# የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ፤



# የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ።

# ኦሪት ፡ ዘፍጥረት ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ በመጀመሪያ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰማይንና ፡
፪ ምድርን ፡ ፈጠረ ። ምድርም ፡ ባዶ ፡ ነበረች ፥
አንዳችም ፡ አልነበረባትም ፤ ጨለማም ፡ በጥ
ልቁ ፡ ላይ ፡ ነበረ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡
፫ በውኃ ፡ ላይ ፡ ሰፍፎ ፡ ነበር ። እግዚአብሔ
ርም ፡— ብርሃን ፡ ይሁን ፡ አለ ፤ ብርሃንም ፡ ሆነ ።
፬ እግዚአብሔርም ፡ ብርሃኑ ፡ መልካም ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ አየ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ብርሃንንና ፡ ጨለ
፭ ማን ፡ ለየ ። እግዚአብሔርም ፡ ብርሃኑን ፡ ቀን ፡
ብሎ ፡ ጠራው ፥ ጨለማውንም ፡ ሌሊት ፡ አለው ።
ማታም ፡ ሆነ ፡ ጥዋትም ፡ ሆነ ፥ አንድ ፡ ቀን ።

፮ እግዚአብሔርም ፡— በውኆች ፡ መካከል ፡
ጠፈር ፡ ይሁን ፥ በውኃና ፡ በውኃ ፡ መካከልም ፡
፯ ይክፈል ፡ አለ ። እግዚአብሔርም ፡ ጠፈርን ፡
አደረገ ፥ ከጠፈር ፡ በታችና ፡ ከጠፈር ፡ በላይ ፡
ያሉትንም ፡ ውኆች ፡ ለየ ፤ እንዲሁም ፡ ሆነ ።
፰ እግዚአብሔር ፡ ጠፈርን ፡ ሰማይ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።
ማታም ፡ ሆነ ፡ ጥዋትም ፡ ሆነ ፥ ሁለተኛ ፡ ቀን ።

፱ እግዚአብሔርም ፡— ከሰማይ ፡ በታች ፡ ያለው ፡
ውኃ ፡ በአንድ ፡ ስፍራ ፡ ይሰብሰብ ፥ የብሱም ፡
፲ ይገለጥ ፡ አለ ፤ እንዲሁም ፡ ሆነ ። እግዚአብሔ
ርም ፡ የብሱን ፡ ምድር ፡ ብሎ ፡ ጠራው ፤ የውኃ ፡
መከማቻውንም ፡ ባሕር ፡ አለው ፤ እግዚአብሔ
፲፩ ርም ፡ ያ ፡ መልካም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አየ ። እግዚ
አብሔርም ፡— ምድር ፡ ዘርን ፡ የሚሰጥ ፡ ሣር
ንና ፡ ቡቃያን ፡ በምድርም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ወገኑ ፡
ዘሩ ፡ ያለበትን ፡ ፍሬን ፡ የሚያፈራ ፡ ዛፍን ፡ ታብ
፲፪ ቅል ፡ አለ ፤ እንዲሁም ፡ ሆነ ። ምድርም ፡ ዘርን ፡
የሚሰጥ ፡ ሣርንና ፡ ቡቃያን ፡ እንደ ፡ ወገኑ ፡
ዘሩም ፡ ያለበትን ፡ ፍሬን ፡ የሚያፈራ ፡ ዛፍን ፡
እንደ ፡ ወገኑ ፡ አበቀለች ። እግዚአብሔርም ፡
፲፫ ያ ፡ መልካም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አየ ። ማታም ፡
ሆነ ፡ ጥዋትም ፡ ሆነ ፥ ሦስተኛ ፡ ቀን ።

፲፬ እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡— ቀንና ፡ ሌሊትን ፡
ይለዩ ፡ ዘንድ ፡ ብርሃናት ፡ በሰማይ ፡ ጠፈር ፡
ይሁኑ ፤ ለምልክቶች ፡ ለዘመኖች ፡ ለዕለታት ፡
፲፭ ለዓመታትም ፡ ይሁኑ ፤ በምድር ፡ ላይ ፡ ያበሩ ፡
ዘንድ ፡ በሰማይ ፡ ጠፈር ፡ ብርሃናት ፡ ይሁኑ ፤
፲፮ እንዲሁም ፡ ሆነ ። እግዚአብሔርም ፡ ሁለት ፡
ታላላቆች ፡ ብርሃናትን ፡ አደረገ ፤ ትልቁ ፡ ብር
ሃን ፡ በቀን ፡ እንዲሠለጥን ፥ ትንሹም ፡ ብርሃን ፡
በሌሊት ፡ እንዲሠለጥን ፤ ከዋክብትንም ፡ ደግሞ ፡
፲፯ አደረገ ። እግዚአብሔርም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡
ያበሩ ፡ ዘንድ ፡ በሰማይ ፡ ጠፈር ፡ አኖራቸው ፤
፲፰ በቀንም ፡ በሌሊትም ፡ እንዲሠለጥኑ ፥ ብርሃን
ንና ፡ ጨለማንም ፡ እንዲለዩ ፤ እግዚአብሔርም ፡
፲፱ ያ ፡ መልካም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አየ ። ማታም ፡ ሆነ ፡
ጥዋትም ፡ ሆነ ፥ አራተኛ ፡ ቀን ።

፳ እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡— ውኃ ፡ ሕያው ፡
ነፍስ ፡ ያላቸውን ፡ ተንቀሳቃሾች ፡ ታስገኝ ፥ ወፎ
ችም ፡ ከምድር ፡ በላይ ፡ ከሰማይ ፡ ጠፈር ፡ በታች ፡
፳፩ ይብረሩ ። እግዚአብሔርም ፡ ታላላቆች ፡ አንበ
ሪዎችን ፥ ውኃይቱ ፡ እንደ ፡ ወገኑ ፡ ያስገኘቻ
ቸውንም ፡ ተንቀሳቃሾቹን ፡ ሕያዋን ፡ ፍጥረ
ታት ፡ ሁሉ ፥ እንደ ፡ ወገኑ ፡ የሚበሩትንም ፡
ወፎች ፡ ሁሉ ፡ ፈጠረ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ያ ፡
፳፪ መልካም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አየ ። እግዚአብሔርም ፡
እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ባረካቸው ፡— ብዙ ፥ ተባዙም ፥
የባሕርንም ፡ ውኃ ፡ ሙሉአት ፤ ወፎችም ፡ በም
፳፫ ድር ፡ ላይ ፡ ይብዙ ። ማታም ፡ ሆነ ፡ ጥዋትም ፡
ሆነ ፥ አምስተኛ ፡ ቀን ።

፳፬ እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡— ምድር ፡ ሕያዋን ፡
ፍጥረታትን ፡ እንደ ፡ ወገኑ ፥ እንስሳትንና ፡ ተን
ቀሳቃሾችን ፡ የምድር ፡ አራዊትንም ፡ እንደ ፡
፳፭ ወገኑ ፥ ታውጣ ፤ እንዲሁም ፡ ሆነ ። እግዚአ
ብሔር ፡ የምድር ፡ አራዊትን ፡ እንደ ፡ ወገኑ ፡
አደረገ ፥ እንስሳውንም ፡ እንደ ፡ ወገኑ ፥ የመ
ሬት ፡ ተንቀሳቃሾችንም ፡ እንደ ፡ ወገኑ ፡ አደ
ረገ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ያ ፡ መልካም ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ አየ ።

፳፮ እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡— ሰውን ፡ በመልካ
ችን ፡ እንደ ፡ ምሳሌአችን ፡ እንፍጠር ፤ የባሕር ፡
ዓሦችንና ፡ የሰማይ ፡ ወፎችን ፥ እንስሳትንና ፡
ምድርን ፡ ሁሉ ፥ በምድር ፡ ላይ ፡ የሚንቀሳቀሱ
፳፯ ትንም ፡ ሁሉ ፡ ይግዙ ። እግዚአብሔርም ፡
ሰውን ፡ በመልኩ ፡ ፈጠረ ፤ በእግዚአብሔር ፡
መልክ ፡ ፈጠረው ፤ ወንድና ፡ ሴት ፡ አድርጎ ፡
፳፰ ፈጠራቸው ። እግዚአብሔርም ፡ ባረካቸው ፥
እንዲህም ፡ አላቸው ፡— ብዙ ፥ ተባዙ ፥ ምድር
ንም ፡ ሙሉአት ፥ ግዙአትም ፤ የባሕርን ፡ ዓሦ
ችና ፡ የሰማይን ፡ ወፎች ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የሚ
ንቀሳቀሱትንም ፡ ሁሉ ፡ ግዙአቸው ።
፳፱ እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡— እነሆ ፡ መብል ፡ ይሆ
ናችሁ ፡ ዘንድ ፡ በምድር ፡ ፊት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ዘሩ ፡
በእርሱ ፡ ያለውን ፡ ሐመልማል ፡ ሁሉ ፥ የዛፍን ፡
ፍሬ ፡ የሚያፈራውንና ፡ ዘር ፡ ያለውንም ፡ ዛፍ ፡
፴ ሁሉ ፡ ሰጠኋችሁ ፤ ለምድርም ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ፥
ለሰማይም ፡ ወፎች ፡ ሁሉ ፥ ሕያው ፡ ነፍስ ፡ ላላ
ቸው ፡ ለምድር ፡ ተንቀሳቃሾችም ፡ ሁሉ ፡ የሚ
በቅለው ፡ ሐመልማል ፡ ሁሉ ፡ መብል ፡ ይሁንላ
፴፩ ቸው ፤ እንዲሁም ፡ ሆነ ። እግዚአብሔርም ፡
ያደረገውን ፡ ሁሉ ፡ አየ ፥ እነሆም ፡ እጅግ ፡ መል
ካም ፡ ነበረ ። ማታም ፡ ሆነ ፡ ጥዋትም ፡ ሆነ ፥
ስድስተኛ ፡ ቀን ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ሰማይና ፡ ምድር ፡ ሠራዊታቸውም ፡ ሁሉ ፡
፪ ተፈጸሙ ። እግዚአብሔርም ፡ የሠራውን ፡ ሥራ ፡
በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ፈጸመ ፤ በሰባተኛውም ፡

፫፤ ቀን ፡ ከሠራው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ዐረፈ ። እግዚ
አብሔርም ፡ ሰባተኛውን ፡ ቀን ፡ ባረከው ፡ ቀደ
ሰውም ፤ እግዚአብሔር ፡ ሊያደርገው ፡ ከፈጠ
ረው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ ዐርፎአልና ።
፬፤ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡
ባደረገ ፡ ቀን ÷ በተፈጠሩ ፡ ጊዜ ፡ የሰማይና ፡ የም
፭፤ ድር ፡ ልደት ፡ ይህ ፡ ነው ። የሜዳ ፡ ቍጥቋጠ ፡
ሁሉ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ገና ፡ አልነበረም ፤ የሜዳ
ውም ፡ ቡቃያ ፡ ሁሉ ፡ ገና ፡ አልበቀለም ፡ ነበር ፤
እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አላ
ዘነበም ፡ ነበርና ÷ ምድርንም ፡ የሚሠራበት ፡
፮፤ ሰው ፡ አልነበረም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ጉም ፡ ከምድር ፡
ትወጣ ፡ ነበር ÷ የምድርንም ፡ ፊት ፡ ሁሉ ፡
፯፤ ታጠጣ ፡ ነበር ። እግዚአብሔር ፡ አምላክም ፡
ሰውን ፡ ከምድር ፡ አፈር ፡ አበጀው ፤ በአፍንጫ
ውም ፡ የሕይወት ፡ እስትንፋስን ፡ እፍ ፡ አለበት ፤
ሰውም ፡ ሕያው ፡ ነፍስ ፡ ያለው ፡ ሆነ ።
፰፤ እግዚአብሔር ፡ አምላክም ፡ በምሥራቅ ፡ በዔ
ድን ፡ ገነትን ፡ ተከለ ፡ የፈጠረውንም ፡ ሰው ፡
፱፤ ከዚያው ፡ አኖረው ። እግዚአብሔር ፡ አምላ
ክም ፡ ለማየት ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘውን ÷ ለመብላ
ትም ፡ መልካም ፡ የሆነውን ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ከም
ድር ፡ አበቀለ ፤ በገነትም ፡ መካከል ፡ የሕይወ
ትን ፡ ዛፍ ÷ መልካምንና ፡ ክፉን ፡ የሚያስታው
፲፤ ቀውንም ፡ ዛፍ ፡ አበቀለ ። ወንዝም ፡ ገነትን ፡
ያጠጣ ፡ ዘንድ ፡ ከዔድን ፡ ይወጣ ፡ ነበር ፤ ከዚ
፲፩፤ ያም ፡ ለአራት ፡ ክፍል ፡ ይከፈል ፡ ነበር ። የአ
ንደኛው ፡ ወንዝ ፡ ስም ፡ ፊሶን ፡ ነው ፤ እርሱም ፡
ወርቅ ፡ የሚገኝበትን ፡ የኤውላጥ ፡ ምድርን ፡ ይከ
፲፪፤ ብባል ፤ የዚያም ፡ ምድር ፡ ወርቅ ፡ ጥሩ ፡ ነው ፤ ከዚ
፲፫፤ ያም ፡ ሉልና ፡ የከበረ ፡ ድንጋይ ፡ ይገኛል ። የሁ
ለተኛውም ፡ ወንዝ ፡ ስም ፡ ግዮን ፡ ነው ፤ እር
ሱም ፡ የኢትዮጵያን ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ይከብባል ።
፲፬፤ የሦስተኛውም ፡ ወንዝ ፡ ስም ፡ ጤግሮስ ፡ ነው ፤
እርሱም ፡ በአሦር ፡ ምሥራቅ ፡ የሚኼድ ፡ ነው ።
፲፭፤ አራተኛውም ፡ ወንዝ ፡ ኤፍራጥስ ፡ ነው ። እግ
ዚአብሔር ፡ አምላክም ፡ ሰውን ፡ ወስዶ ፡ ያበጃ
ትም ፡ ይጠብቃትም ፡ ዘንድ ፡ በዔድን ፡ ገነት ፡
፲፮፤ አኖረው ። እግዚአብሔር ፡ አምላክም ፡ ሰውን ፡
እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘዘው ፡— ከገነት ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡
፲፯፤ ትበላለህ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ መልካምንና ፡ ክፉን ፡
ከሚያስታውቀው ፡ ዛፍ ፡ አትብላ ፤ ከእርሱ ፡
በበላህ ፡ ቀን ፡ ሞትን ፡ ትሞታለህና ።
፲፰፤ እግዚአብሔር ፡ አምላክም ፡ አለ ፡— ሰው ፡
ብቻውን ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ መልካም ፡ አይደለም ፤
፲፱፤ የሚመቸውን ፡ ረዳት ፡ እንፍጠርለት ። እግ
ዚአብሔር ፡ አምላክም ፡ የምድር ፡ አራዊት
ንና ፡ የሰማይ ፡ ወፎችን ፡ ሁሉ ፡ ከመሬት ፡ አደ
ረገ ፤ በምን ፡ ስም ፡ እንደሚጠራቸውም ፡ ያይ ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ አዳም ፡ አመጣቸው ፤ አዳምም ፡
ሕያው ፡ ነፍስ ፡ ላለው ፡ ሁሉ ፡ በስሙ ፡ እንደ ፡
፳፤ ጠራው ፡ ስሙ ፡ ያው ፡ ሆነ ። አዳምም ፡ ለእን
ስሳት ፡ ሁሉ ÷ ለሰማይ ፡ ወፎችም ፡ ሁሉ ÷ ለም
ድር ፡ አራዊትም ፡ ሁሉ ፡ ስም ፡ አወጣላቸው ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ለአዳም ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ያለ ፡
ረዳት ፡ አልተገኘለትም ፡ ነበር ። እግዚአብሔር ፡ ፳፩፤
አምላክም ፡ በአዳም ፡ ከባድ ፡ እንቅልፍን ፡ ጣለ
በት ÷ አንቀላፋም ፤ ከጎኑም ፡ አንዲት ፡ አጥንትን ፡
ወስዶ ፡ ስፍራውን ፡ በሥጋ ፡ ዘጋው ። እግዚአ ፳፪፤
ብሔር ፡ አምላክም ፡ ከአዳም ፡ የወሰዳትን ፡ አጥ
ንት ፡ ሴት ፡ አድርጎ ፡ ሠራት ፤ ወደ ፡ አዳምም ፡
አመጣት ። አዳምም ፡ አለ ፡— ይህች ፡ አጥንት ፡ ፳፫፤
ከአጥንቴ ፡ ናት ÷ ሥጋም ፡ ከሥጋዬ ፡ ናት ፤ እር
ስዋ ፡ ከወንድ ፡ ተገኝታለችና ፡ ሴት ፡ ትባል ።
ስለዚህ ፡ ሰው ፡ አባቱንና ፡ እናቱን ፡ ይተዋል ÷ ፳፬፤
በሚስቱም ፡ ይጣበቃል ፤ ሁለቱም ፡ አንድ ፡
ሥጋ ፡ ይሆናሉ ። አዳምና ፡ ሚስቱ ፡ ሁለቱም ፡ ፳፭፤
ዕራቁታቸውን ፡ ነበሩ ÷ አይተፋፈሩም ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

እባብም ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ከፈጠ ፩፤
ረው ፡ ከምድር ፡ አውሬ ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ተን
ኰለኛ ፡ ነበረ ። ሴቲቱንም ፡— በውኑ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ከገነት ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ እንዳትበሉ ፡
አዝዞአልን ? አላት ። ሴቲቱም ፡ ለእባቡ ፡ አለ ፪፤
ችው ፡— በገነት ፡ ካለው ፡ ከዛፍ ፡ ፍሬ ፡ እንበ
ላለን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በገነት ፡ መካከል ፡ ካለው ፡ ፫፤
ከዛፉ ፡ ፍሬ ÷ እግዚአብሔር ፡ አለ ፡— እንዳት
ሞቱ ፡ ከእርሱ ፡ አትብሉ ፡ አትንኩትም ። እባ ፬፤
ብም ፡ ለሴቲቱ ፡ አላት ፡— ሞትን ፡ አትሞቱም ፤
ከእርስዋ ፡ በበላችሁ ፡ ቀን ፡ ዓይኖቻችሁ ፡ እን ፭፤
ዲከፈቱ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ መልካም
ንና ፡ ክፉን ፡ የምታውቁ ፡ እንድትሆኑ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ስለሚያውቅ ፡ ነው ፡ እንጂ ። ሴቲቱም ፡ ፮፤
ዛፉ ፡ ለመብላት ፡ ያማረ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ ለዓይ
ንም ፡ እንደሚያስጐመጅ ÷ ለጥበብም ፡ መልካም ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ አየች ፤ ከፍሬውም ፡ ወሰደችና ፡
በላች ፤ ለባልዋም ፡ ደግሞ ፡ ሰጠችው ፡ እር
ሱም ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ በላ ። የሁለቱም ፡ ዓይ ፯፤
ኖች ፡ ተከፈቱ ÷ እነርሱም ፡ ዕራቁታቸውን ፡
እንደ ፡ ሆኑ ፡ አወቁ ፤ የበለስንም ፡ ቅጠሎች ፡
ሰፍተው ፡ ለእነርሱ ፡ ለራሳቸው ፡ ግልድም ፡ አደ
ረጉ ። እነርሱም ፡ ቀኑ ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡ የእግዚ ፰፤
አብሔርን ፡ የአምላክን ፡ ድምፅ ፡ ከገነት ፡ ውስጥ ፡
ሲመላለስ ፡ ሰሙ ፤ አዳምና ፡ ሚስቱም ፡ ከእግ
ዚአብሔር ፡ ከአምላክ ፡ ፊት ፡ በገነት ፡ ዛፎች ፡
መካከል ፡ ተሸሸጉ ።
እግዚአብሔር ፡ አምላክም ፡ አዳምን ፡ ጠርቶ ፡— ፱፤
ወዴት ፡ ነህ ? አለው ። እርሱም ፡ አለ ፡— በገ ፲፤
ነት ፡ ድምፅህን ፡ ሰማሁ ፤ ዕራቁቴንም ፡ ስለ ፡
ሆንሁ ፡ ፈራሁ ÷ ተሸሸግሁም ። እግዚአብሔ ፲፩፤
ርም ፡ አለው ፡— ዕራቁትህን ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡
ማን ፡ ነገረህ ? ከእርሱ ፡ እንዳትበላ ፡ ካዘዝሁህ ፡
ዛፍ ፡ በውኑ ፡ በላህን ? አዳምም ፡ አለ ፡— ከእኔ ፡ ፲፪፤
ጋር ፡ እንድትሆን ፡ የሰጠኸኝ ፡ ሴት ፡ እርስዋ ፡
ከዛፉ ፡ ሰጠችኝና ፡ በላሁ ። እግዚአብሔር ፡ አም ፲፫፤
ላክም ፡ ሴቲቱን ፡— ይህ ፡ ያደረግሽው ፡ ምን
ድር ፡ ነው ? አላት ። ሴቲቱም ፡ አለች ፡— እባብ ፡

፲፬ አሳተኝና ፡ በላሁ ። እግዚአብሔር ፡ አምላ
ክም ፡ እባቡን ፡ አለው ፡— ይህን ፡ ስላደረግህ ፡
ከእንስሳት ፡ ከምድር ፡ አራዊትም ፡ ሁሉ ፡ ተለ
ይተህ ፡ አንተ ፡ የተረገምህ ፡ ትሆናለህ ፤ በሆድ
ህም ፡ ትሄዳለህ ፥ አፈርንም ፡ በሕይወትህ ፡ ዘመን ፡
፲፭ ሁሉ ፡ ትበላለህ ። በአንተና ፡ በሴቲቱ ፡ መከከል ፥
በዘርህና ፡ በዘርዋም ፡ መከከል ፡ ጠላትነትን ፡
አደርጋለሁ ፤ እርሱ ፡ ራስህን ፡ ይቀጠቅጣል ፥
፲፮ አንተም ፡ ሰኰናውን ፡ ትቀጠቅጣለህ ። ለሴ
ቲቱም ፡ አለ ፡— በፀነስሽ ፡ ጊዜ ፡ ጭንቅሽን ፡
እጅግ ፡ አበዛለሁ ፤ በጭንቅ ፡ ትወልጃለሽ ፤
ፈቃድሽም ፡ ወደ ፡ ባልሽ ፡ ይሆናል ፥ እርሱም ፡
፲፯ ገዥሽ ፡ ይሆናል ። አዳምንም ፡ አለው ፡— የሚ
ስትህን ፡ ቃል ፡ ሰምተሃልና ፥ ከእርሱ ፡ እንዳ
ትበላ ፡ ከዘዝሁህ ፡ ዛፍም ፡ በልተሃልና ፡ ምድር ፡
ከአንተ ፡ የተነሣ ፡ የተረገመች ፡ ትሁን ፤ በሕይ
ወት ፡ ዘመንህም ፡ ሁሉ ፡ በድካም ፡ ከእርስዋ ፡
፲፰ ትበላለህ ፤ እሾህንና ፡ አሜከላን ፡ ታበቅልብ
፲፱ ሃለች ፤ የምድርንም ፡ ቡቃያ ፡ ትበላለህ ። ወደ ፡
ወጣህበት ፡ መሬት ፡ እስክትመለስ ፡ ድረስ ፡ በፊ
ትህ ፡ ወዝ ፡ እንጀራን ፡ ትበላለህ ፤ አፈር ፡ ነህና ፥
፳ ወደ ፡ አፈርም ፡ ትመለሳለህና ። አዳምም ፡ ለሚ
ስቱ ፡ ሔዋን ፡ ብሎ ፡ ስም ፡ አወጣ ፥ የሕያዋን ፡
፳፩ ሁሉ ፡ እናት ፡ ናትና ። እግዚአብሔር ፡ አምላ
ክም ፡ ለአዳምና ፡ ለሚስቱ ፡ የቁርበትን ፡ ልብስ ፡
አደረገላቸው ፥ አለበሳቸውም ።

፳፪ እግዚአብሔር ፡ አምላክም ፡ አለ ፡— እነሆ
አዳም ፡ መልካምንና ፡ ክፉን ፡ ለማወቅ ፡ ከእኛ ፡
እንደ ፡ አንዱ ፡ ሆነ ፤ አሁንም ፡ እጁን ፡ እንዳ
ይዘረጋ ፥ ደግሞም ፡ ከሕይወት ፡ ዛፍ ፡ ወስዶ ፡
እንዳይበላ ፥ ለዘላለምም ፡ ሕያው ፡ ሆኖ ፡ እንዳይ
፳፫ ኖር ፤ ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ከዔ
ድን ፡ ገነት ፡ አስወጣው ፥ የተገኘባትን ፡ መሬት ፡
፳፬ ያርስ ፡ ዘንድ ። አዳምንም ፡ አስወጣው ፥ ወደ ፡
ሕይወት ፡ ዛፍ ፡ የሚወስደውንም ፡ መንገድ ፡
ለመጠበቅ ፡ ኪሩቤልንና ፡ የምትገለባበጥ ፡ የነ
በልባል ፡ ሰይፍን ፡ በዔድን ፡ ገነት ፡ ምሥራቅ ፡
አስቀመጠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ አዳምም ፡ ሚስቱን ፡ ሔዋንን ፡ አወቀ ፤ ፀነ
ሰችም ፥ ቃየንንም ፡ ወለደች ። እርስዋም ፡—
ወንድ ፡ ልጅ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ አገኘሁ ፡ አለች ።
፪ ደግሞም ፡ ወንድሙን ፡ አቤልን ፡ ወለደች ።
አቤልም ፡ በግ ፡ ጠባቂ ፡ ነበረ ፤ ቃየንም ፡ ምድ
፫ ርን ፡ የሚያርስ ፡ ነበረ ። ከብዙ ፡ ቀን ፡ በኋላም ፡
ቃየን ፡ ከምድር ፡ ፍሬ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሥዋ
፬ ዕትን ፡ አቀረበ ፤ አቤልም ፡ ደግሞ ፡ ከበጎቹ ፡ በኵ
ራትና ፡ ከስቡ ፡ አቀረበ ። እግዚአብሔርም ፡
ወደ ፡ አቤልና ፡ ወደ ፡ መሥዋዕቱ ፡ ተመለከተ ፤
፭ ወደ ፡ ቃየንና ፡ ወደ ፡ መሥዋዕቱ ፡ ግን ፡ አል
ተመለከተም ። ቃየንም ፡ እጅግ ፡ ተናደደ ፡
፮ ፊቱም ፡ ጠቆረ ። እግዚአብሔርም ፡ ቃየንን ፡
አለው ፡— ለምን ፡ ተናደድህ ? ለምንስ ፡ ፊትህ ፡
ጠቆረ ? መልካም ፡ ብታደርግ ፡ ፊትህ ፡ የሚ ፯
በራ ፡ አይደለምን ? መልካም ፡ ባታደርግ ፡ ግን ፡
ኃጢአት ፡ በደጅ ፡ ታደባለች ፤ ፈቃድዋም ፡
ወደ ፡ አንተ ፡ ነው ፥ አንተ ፡ ግን ፡ በእርስዋ ፡
ንገሥባት ። ቃየንም ፡ ወንድሙን ፡ አቤልን ፡— ፰
ና ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡ እንሂድ ፡ አለው ። በሜዳም ፡
ሳሉ ፡ ቃየን ፡ በወንድሙ ፡ በአቤል ፡ ላይ ፡ ተነ
ሣበት ፥ ገደለውም ።

፱ እግዚአብሔርም ፡ ቃየንን ፡ አለው ፡— ወንድ
ምህ ፡ አቤል ፡ ወዴት ፡ ነው ? እርሱም ፡ አለ ፡—
አላውቅም ፤ የወንድሜ ፡ ጠባቂው ፡ እኔ ፡ ነኝን ?
፲ አለውም ፡— ምን ፡ አደረግህ ? የወንድምህ ፡
የደሙ ፡ ድምፅ ፡ ከምድር ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይጮ
፲፩ ኻል ። አሁንም ፡ የወንድምህን ፡ ደም ፡ ከእ
ጅህ ፡ ለመቀበል ፡ አፍዋን ፡ በከፈተች ፡ በም
፲፪ ድር ፡ ላይ ፡ አንተ ፡ የተረገምህ ፡ ነህ ። ምድር
ንም ፡ ባረስህ ፡ ጊዜ ፡ እንግዲህ ፡ ኃይልዋን ፡
አትሰጥህም ፤ በምድርም ፡ ላይ ፡ ኰብላይና ፡
፲፫ ተቅበዝባዥ ፡ ትሆናለህ ። ቃየንም ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ አለው ፡— ኃጢአቴ ፡ ልሸከማት ፡ የማ
፲፬ ልችላት ፡ ታላቅ ፡ ናት ። እነሆ ፡ ዛሬ ፡ ከምድር ፡
ፊት ፡ አሳደድኸኝ ፤ ከፊትህም ፡ እሰወራለሁ ፤
በምድርም ፡ ላይ ፡ ኰብላይና ፡ ተቅበዝባዥ ፡
እሆናለሁ ፤ የሚያገኘኝም ፡ ሁሉ ፡ ይገድለኛል ።
፲፭ እግዚአብሔርም ፡ እርሱን ፡ አለው ፡— እንግ
ዲህ ፡ ቃየንን ፡ የገደለ ፡ ሁሉ ፡ ሰባት ፡ እጥፍ ፡
ይበቀልበታል ። እግዚአብሔርም ፡ ቃየንን ፡
ያገኘው ፡ ሁሉ ፡ እንዳይገድለው ፡ ምልክት ፡
አደረገለት ።

፲፮ ቃየንም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ወጣ ፤ ከዔ
ድንም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ በኖድ ፡ ምድር ፡ ተቀ
፲፯ መጠ ። ቃየንም ፡ ሚስቱን ፡ አወቀ ፤ ፀነሰችም ፥
ሄኖሕንም ፡ ወለደች ። ከተማም ፡ ሠራ ፥ የከ
ተማይቱንም ፡ ስም ፡ በልጁ ፡ ስም ፡ ሄኖሕ ፡
፲፰ አላት ። ሄኖሕም ፡ ጋይዳድን ፡ ወለደ ፤ ጋይ
ዳድም ፡ ሜኤልን ፡ ወለደ ፤ ሜኤልም ፡ ማቱ
ሣኤልን ፡ ወለደ ፤ ማቱሣኤልም ፡ ላሜሕን ፡
ወለደ ።

፲፱ ላሜሕም ፡ ለራሱ ፡ ሁለት ፡ ሚስቶችን ፡ አገባ ፤
የአንዲቱ ፡ ስም ፡ ዓዳ ፥ የሁለተኛይቱ ፡ ስም ፡
፳ ሴላ ፡ ነበረ ። ዓዳም ፡ ያባልን ፡ ወለደች ፤ እር
ሱም ፡ በድንኳን ፡ የሚቀመጡት ፡ የዘላኖች ፡
፳፩ አባት ፡ ነበረ ። የወንድሙም ፡ ስም ፡ ዩባል ፡
ነበረ ፤ እርሱም ፡ በገናንና ፡ መለከትን ፡ ለሚ
፳፪ ይዙ ፡ አባት ፡ ነበረ ። ሴላም ፡ ደግሞ ፡ ከናስና ፡
ከብረት ፡ የሚቀጠቀጥ ፡ ዕቃን ፡ የሚሠራውን ፡
ቱባልቃይንን ፡ ወለደች ። የቱባልቃይንም ፡
፳፫ እኅት ፡ ናዕማ ፡ ነበረች ። ላሜሕም ፡ ለሚስ
ቶቹ ፡ ለዓዳና ፡ ለሴላ ፡ አላቸው ፡— እናንተ ፡ የላ
ሜሕ ፡ ሚስቶች ፡ ቃሌን ፡ ስሙ ፥ ነገሬንም ፡
አድምጡ ፤ እኔ ፡ ጕልማሳውን ፡ ለቍስሌ ፥ ብላ
፳፬ ቴናውንም ፡ ለመወጋቴ ፡ ገድዬዋለሁና ፤ ቃየ
ንን ፡ ሰባት ፡ እጥፍ ፡ ይበቀሉታል ፤ ላሜሕን ፡
ግን ፡ ሰባ ፡ ሰባት ፡ እጥፍ ።

፳፭ አዳም ፡ ደግሞ ፡ ሚስቱን ፡ አወቀ ፤ ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ወለደች ። ስሙንም ፡— ቃየን ፡ በገደለው ፡ በአቤል ፡ ፋንታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሌላ ፡ ዘር ፡ ተክቶልኛል ፡ ስትል ፡ ሴት ፡ አለችው ። ፳፮ ለሴት ፡ ደግሞ ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ተወለደለት ፤ ስሙንም ፡ ሄኖስ ፡ አለው ፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ መጠራት ፡ ተጀመረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ የአዳም ፡ የትውልዱ ፡ መጽሐፍ ፡ ይህ ፡ ነው ። እግዚአብሔር ፡ አዳምን ፡ በፈጠረ ፡ ቀን ፡ በእ ፪ ግዚአብሔር ፡ ምሳሌ ፡ አደረገው ፤ ወንድና ፡ ሴት ፡ አድርጎ ፡ ፈጠራቸው ÷ ባረካቸውም ። ስማቸውንም ፡ በፈጠረበት ፡ ቀን ፡ አዳም ፡ ብሎ ፡ ፫ ጠራቸው ። አዳምም ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ÷ ልጅንም ፡ በምሳሌው ፡ እንደ ፡ መልኩ ፡ ወለደ ፤ ስሙንም ፡ ሴት ፡ ብሎ ፡ ጠራው ። ፬ አዳምም ፡ ሴትን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ የኖረው ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ወንዶችንም ፡ ሴቶ ፭ ችንም ፡ ወለደ ። አዳምም ፡ የኖረበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ሞተም ።

፮ ሴትም ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ኖረ ÷ ፯ ሄኖስንም ፡ ወለደ ፤ ሴትም ፡ ሄኖስን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ የኖረው ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ። ፰ ሴትም ፡ የኖረበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ሞተም ።

፱ ሄኖስም ፡ መቶ ፡ ዘጠና ፡ ዓመት ፡ ኖረ ÷ ቃይ ፲ ናንንም ፡ ወለደ ፤ ሄኖስም ፡ ቃይናንን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ የኖረው ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ፲፩ ወለደ ። ሄኖስም ፡ የኖረበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ሞተም ።

፲፪ ቃይናንም ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ÷ መላል ፲፫ ኤልንም ፡ ወለደ ፤ ቃይናንም ፡ መላልኤልን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ የኖረው ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ። ፲፬ ቃይናንም ፡ የኖረበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ አሥር ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ሞተም ።

፲፭ መላልኤልም ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ፲፮ ኖረ ÷ ያሬድንም ፡ ወለደ ፤ መላልኤልም ፡ ያሬድን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ የኖረው ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ፲፯ ወለደ ። መላልኤልም ፡ የኖረበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ስምንት ፡ መቶ ፡ ዘጠና ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ሞተም ።

፲፰ ያሬድም ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ኖረ ÷ ፲፱ ሄኖክንም ፡ ወለደ ፤ ያሬድም ፡ ሄኖክን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ የኖረው ፡ ስምንት ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ ፳ ሆነ ፤ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ። ያሬድም ፡ የኖረበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ሞተም ።

፳፩ ሄኖክም ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ኖረ ÷ ማቱሳላንም ፡ ወለደ ፤ ፳፪ ሄኖክም ፡ አካሄዱን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ አደረገ ፤ ማቱሳላንም ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ የኖረው ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ። ፳፫ ሄኖክም ፡ የኖረበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ። ፳፬ ሄኖክም ፡ አካሄዱን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ ስላደረገ ፡ አልተገኘም ፤ እግዚአብሔር ፡ ወስዶታልና ።

፳፭ ማቱሳላም ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ፳፮ ኖረ ÷ ላሜሕንም ፡ ወለደ ፤ ማቱሳላም ፡ ላሜሕን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ የኖረው ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ። ፳፯ ማቱሳላም ፡ የኖረበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ ዘጠኝ ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ሞተም ።

፳፰ ላሜሕም ፡ መቶ ሰማንያ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ፳፱ ኖረ ÷ ልጅንም ፡ ወለደ ። ስሙንም ፡— እግዚአብሔር ፡ በረገማት ፡ ምድር ፡ ከተግባራችንና ፡ ከእጅ ፡ ሥራችን ፡ ይህ ፡ ያሳርፈናል ፡ ሲል ፡ ፴ ኖኅ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ። ላሜሕም ፡ ኖኅን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ የኖረው ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ። ፴፩ ላሜሕ ፡ የኖረበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ሞተም ።

፴፪ ኖኅም ፡ የአምስት ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ኖኅም ፡ ሴምን ፡ ካምን ፡ ያፌትንም ፡ ወለደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ሰዎች ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ መብዛት ፡ በጀመሩ ፡ ጊዜ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ተወለዱላቸው ፤ ፪ የእግዚአብሔር ፡ ልጆችም ፡ የሰውን ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ መልካሞች ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ አዩ ፤ ከመረጡአቸውም ፡ ሁሉ ፡ ሚስቶችን ፡ ለራሳቸው ፡ ወሰዱ ። ፫ እግዚአብሔርም ፡— መንፈሴ ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ለዘላለም ፡ አይኖርም ÷ እርሱ ፡ ሥጋ ፡ ነውና ፤ ዘመኖቹም ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ዓመት ፡ ይሆናሉ ፡ አለ ። ፬ በእነዚያ ፡ ወራት ፡ ኔፊሊም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ነበሩ ፤ ደግሞም ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ የሰውን ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ ልጆችን ፡ ወለዱላቸው ፤ እነርሱም ፡ በዱሮ ፡ ዘመን ፡ ስማቸው ፡ የታወቀ ፡ ኃያላን ፡ ሆኑ ።

፭ እግዚአብሔርም ፡ የሰው ፡ ክፋት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ በዛ ÷ የልቡ ፡ አሳብ ፡ ምኞትም ፡ ሁልጊዜ ፡ ፈጽሞ ፡ ክፉ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አየ ። ፮ እግዚአብሔርም ፡ ሰውን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በመ ፯ ፍጠሩ ፡ ተጸጸተ ÷ በልቡም ፡ አዘነ ። እግዚአብሔርም ፡— የፈጠርሁትን ፡ ሰው ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ አጠፋለሁ ÷ ከሰው ፡ እስከ ፡ እንስሳ ፡ እስከ ፡ ተንቀሳቃሽም ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ወፍም ፡ ድረስ ፤ ስለ ፡ ፈጠርኋቸው ፡ ተጸጽቼአለሁና ፡ አለ ። ፰ ኖኅ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሞገስን ፡ አገኘ ።

፱ የኖኅ ፡ ትውልድ ፡ እንዲህ ፡ ነው ። ኖኅም ፡

በትውልዱ ፡ ጻድቅ ፡ ፍጹምም ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ኖኅ ፡ አካሄዱን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ አደረገ ። ፲ ፤ ኖኅም ፡ ሦስት ፡ ልጆችን ፡ ሴምን ፡ ካምን ፡ ያፌ ትንም ፡ ወለደ ። ፲፩ ፤ ምድርም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ተበላሸች ፤ ምድርም ፡ ግፍን ፡ ተሞ ላች ። ፲፪ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ምድርን ፡ አየ ፥ እነ ሆም ፡ ተበላሸች ፤ ሥጋን ፡ የለበሰ ፡ ሁሉ ፡ በም ድር ፡ ላይ ፡ ጐንገዱን ፡ አበላሽቶ ፡ ነበርና ።

፲፫ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ኖኅን ፡ አለው ፡— የሥጋ ፡ ሁሉ ፡ ፍጻሜ ፡ በፊቴ ፡ ደርሶአል ፤ ከእነርሱ ፡ የተነሣ ፡ ምድር ፡ በግፍ ፡ ተሞልታለችና ፤ እኔም ፡ እነሆ ፡ ከምድር ፡ ጋር ፡ አጠፋቸዋለሁ ። ፲፬ ፤ ከጎፈር ፡ እንጨት ፡ መርከብን ፡ ለአንተ ፡ ሥራ ፤ በመርከቢቱም ፡ ጉርጆችን ፡ አድርግ ፥ በውስጥም ፡ ፲፭ ፤ በውጭም ፡ በቅጥራን ፡ ለቅልቃት ። እርስዋንም ፡ እንዲህ ፡ ታደርጋታለህ ፤ የመርከቢቱ ፡ ርዝመት ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፥ ወርድዋ ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፥ ፲፮ ፤ ከፍታዋ ፡ ሠላሳ ፡ ክንድ ፡ ይሁን ። ለመርከቢ ቱም ፡ መስኮትን ፡ ታደርጋለህ ፤ ከቁመትዋም ፡ ክንድ ፡ሙሉ ፡ ትተህ ፡ ጨርሳት ፤ የመርከቢቱ ንም ፡ በር ፡ በጎንዋ ፡ አድርግ ፤ ታችኛውንም ፡ ሁለተኛውንም ፡ ሦስተኛውንም ፡ ደርብ ፡ ታደ ፲፯ ፤ ርጋታለህ ። እኔም ፡ እነሆ ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡ የሕይወት ፡ ነፍስ ፡ ያለውን ፡ ሥጋ ፡ ሁሉ ፡ ለማጥ ፋት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የጥፋት ፡ ውኃን ፡ አመጣ ፲፰ ፤ ለሁ ፤ በምድር ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋል ። ቃል ፡ ኪዳኔንም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አቆማለሁ ፤ ወደ ፡ መርከብም ፡ አንተ ፡ ልጆችህንና ፡ ሚስትህን ፡ የልጆችህንም ፡ ሚስቶች ፡ ይዘህ ፡ ትገባለህ ። ፲፱ ፤ ከአንተ ፡ ጋር ፡ በሕይወት ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡ ሥጋ ፡ ካለው ፡ ከሕያው ፡ ሁሉ ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ እያደ ረግህ ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ታገባለህ ፤ ተባትና ፡ ፳ ፤ እንስት ፡ ይሁን ። ከወፍ ፡ እንደ ፡ ወገኑ ፥ ከእ ንስሳም ፡ እንደ ፡ ወገኑ ፥ ከምድር ፡ ተንቀሳቃሽም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ወገኑ ፡ በሕይወት ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ እየሆኑ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ይግቡ ። ፳፩ ፤ ከሚበላውም ፡ መብል ፡ ሁሉ ፡ ለአንተ ፡ ውሰድ ፥ ወደ ፡ አንተም ፡ ትሰበስባለህ ፤ እርሱም ፡ ለአ ፳፪ ፤ ንተም ፡ ለእነርሱም ፡ መብል ፡ ይሆናል ። ኖኅም ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ኖኅን ፡ አለው ፡— አንተ ፡ ቤተ ፡ ሰቦችህን ፡ ሁሉ ፡ ይዘህ ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ግባ ፤ በዚህ ፡ ትውልድ ፡ በፊቴ ፡ ጻድቅ ፡ ሆነህ ፡ ፪-፫ ፤ አይቼሃለሁና ። ከንጹሕ ፡ እንስሳ ፡ ሁሉ ፡ ሰባት ፡ ሰባት ፡ ተባትና ፡ እንስት ፥ ንጹሕ ፡ ካልሆነ ፡ እን ስሳም ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ ተባትና ፡ እንስት ፥ ከሰ ማይ ፡ ወፍ ፡ ደግሞ ፡ ሰባት ፡ ሰባት ፡ ተባትና ፡ እንስት ፡ እያደረግህ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ለዘር ፡ ፬ ፤ ይቀር ፡ ዘንድ ፡ ለአንተ ፡ ትወስዳለህ ። ከሰባት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ አርባ ፡ ቀንና ፡ አርባ ፡ ሌሊት ፡ በም ድር ፡ ላይ ፡ ዝናብ ፡ አዘንባለሁና ፤ የፈጠርሁ ትንም ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ አጠ ፋለሁና ። ፭ ፤ ኖኅም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ፡ አደረገ ። ፮ ፤ ኖኅም ፡ የጥፋት ፡ ውኃ ፡ በም ድር ፡ ላይ ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ የስድስት ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ ዕድሜ ፡ ነበረ ።

፯ ፤ ኖኅም ፡ ስለ ፡ ጥፋት ፡ ውኃ ፡ ልጆቹንና ፡ ሚስ ቱን ፡ የልጆቹንም ፡ ሚስቶች ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ መር ከብ ፡ ገባ ። ፰ ፤ ከንጹሕ ፡ እንስሳ ፡ ንጹሕም ፡ ካል ሆነው ፡ እንስሳ ፥ ከወፎችና ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ከሚንቀሳቀሰውም ፡ ሁሉ ፥ ፱ ፤ እግዚአብሔር ፡ ኖኅን ፡ እንዳዘዘው ፥ ሁለት ፡ ሁለት ፡ ተባትና ፡ እንስት ፡ እየሆኑ ፡ ወደ ፡ ኖኅ ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ውስጥ ፡ ገቡ ። ፲ ፤ ከሰባት ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ የጥ ፋት ፡ ውኃ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ሆነ ። ፲፩ ፤ በኖኅ ፡ ዕድሜ ፡ በስድስተኛው ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ በሁለ ተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአሥራ ፡ ሰባተኛው ፡ ዕለት ፥ በዚያው ፡ ቀን ፡ የታላቁ ፡ ቀላይ ፡ ምን ጮች ፡ ሁሉ ፡ ተነደሉ ፥ የሰማይም ፡ መስኮቶች ፡ ተከፈቱ ፤ ፲፪ ፤ ዝናቡም ፡ አርባ ፡ ቀንና ፡ አርባ ፡ ሌሊት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ሆነ ።

፲፫ ፤ በዚያውም ፡ ቀን ፡ ኖኅ ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ገባ ፥ የኖኅ ፡ ልጆችም ፡ ሴም ፡ ካም ፡ ያፌትና ፡ የኖኅ ፡ ሚስት ፡ ሦስቱም ፡ የልጆቹ ፡ ሚስቶች ፡ ከእ ርሱ ፡ ጋር ፡ ገቡ ። ፲፬ ፤ እነርሱ ፥ አራዊትም ፡ ሁሉ ፡ በየወገናቸው ፥ እንስሳትም ፡ ሁሉ ፡ በየወገና ቸው ፥ በምድር ፡ ላይ ፡ የሚንቀሳቀሱ ፡ ተንቀሳ ቃሾችም ፡ ሁሉ ፡ በየወገናቸው ፥ ወፎችም ፡ ሁሉ ፡ በየወገናቸው ፥ የሚበሩ ፡ ወፎችም ፡ ሁሉ ፥ ፲፭ ፤ ሥጋ ፡ ያላቸው ፡ ሕያዋን ፡ ሁሉ ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ እየሆኑ ፡ ወደ ፡ ኖኅ ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ውስጥ ፡ ገቡ ። ፲፮ ፤ ሥጋ ፡ ካለው ፡ ሁሉ ፡ የገቡትም ፡ ተባ ትና ፡ እንስት ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ ገቡ ፤ ፲፯ ፤ እግዚአብሔርም ፡ በስተ ፡ ኋላው ፡ ዘጋበት ። የጥ ፋትም ፡ ውኃ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አርባ ፡ ቀን ፡ ነበረ ፤ ውኃውም ፡ በዛ ፡ መርከቢቱንም ፡ አነሣ ፥ ከምድርም ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለች ። ፲፰ ፤ ውኃውም ፡ አሸነፈ ፥ በምድር ፡ ላይም ፡ እጅግ ፡ በዛ ፤ መርከቢቱም ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡ ሄደች ። ፲፱ ፤ ውኃ ውም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡ በጣም ፡ አሸ ነፈ ፤ ከሰማይም ፡ በታች ፡ ያሉ ፡ ታላላቆች ፡ ተራ ሮች ፡ ሁሉ ፡ ተሸፈኑ ። ፳ ፤ ውኃው ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ፤ ተራ ሮችም ፡ ተሸፈኑ ። ፳፩ ፤ በምድር ፡ ላይ ፡ ሥጋ ፡ ያለው ፡ የሚንቀሳቀሰው ፡ ሁሉ ፥ ወፉም ፥ እንስሳውም ፥ አራዊቱም ፥ በምድር ፡ ላይ ፡ የሚርመሰመሰው ፡ ተንቀሳቃሹም ፡ ሁሉ ፥ ሰውም ፡ ሁሉ ፡ ጠፋ ። ፳፪ ፤ በየብስ ፡ የነበረው ፡ በአፍንጫው ፡ የሕይወት ፡ ነፍስ ፡ እስትንፋስ ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ ሞተ ። ፳፫ ፤ በም ድር ፡ ላይ ፡ የነበረውም ፡ ሁሉ ፡ ከሰው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ እንስሳ ፡ ድረስ ፥ እስከሚርመሰመሰውም ፡ ሁሉ ፡ ድረስ ፥ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ወፍ ፡ ድረስ ፡ ተደመሰሰ ፤ ከምድርም ፡ ተደመሰሱ ። ኖኅም ፡ አብረውት ፡ በመርከብ ፡ ከነበሩት ፡ ጋር ፡ ብቻ ውን ፡ ቀረ ። ፳፬ ፤ ውኃውም ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ቀን ፡

በምድር ፡ ላይ ፡ አሸነፈ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩፤ እግዚአብሔርም ፡ ኖኅን ፥ በመርከብም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበረውን ፡ አራዊቱን ፡ ሁሉ ፥ እንስሳውንም ፡ ሁሉ ፡ አሰበ ፤ እግዚአብሔርም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ነፋስን ፡ አሳለፈ ፥ ውኃውም ፡ ፪፤ ጐደለ ፤ የቀላዩም ፡ ምንጮች ፡ የሰማይም ፡ መስኮቶች ፡ ተደፈኑ ፥ ዝናብም ፡ ከሰማይ ፡ ተከለ ፫፤ ከለ ፤ ውኃውም ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ እያደር ፡ እያደር ፡ ቀለለ ፥ ከመቶ ፡ አምሳ ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ፬፤ ውኃው ፡ ጐደለ ። መርከቢቱም ፡ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአሥራ ፡ ሰባተኛው ፡ ቀን ፡ በአ ፭፤ ራራት ፡ ተራሮች ፡ ላይ ፡ ተቀመጠች ። ውኃውም ፡ እስከ ፡ አሥረኛው ፡ ወር ፡ ድረስ ፡ ይጐድል ፡ ነበር ፤ በአሥረኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ የተራሮቹ ፡ ራሶች ፡ ተገለጡ ።

፮፤ ከአርባ ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ኖኅ ፡ የሠራውን ፡ የመ ፯፤ ርከቢቱን ፡ መስኮት ፡ ከፈተ ፥ ቁራንም ፡ ሰደደው ፤ እርሱም ፡ ወጣ ፤ ውኃው ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ እስኪደርቅ ፡ ድረስ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ ፰፤ ይበር ፡ ነበር ። ርግብንም ፡ ውኃው ፡ ከምድር ፡ ፊት ፡ ቀልሎ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንድታይ ፡ ከእርሱ ፡ ፱፤ ዘንድ ፡ ሰደዳት ። ነገር ፡ ግን ፡ ርግብ ፡ እግርዋን ፡ የምታሳርፍበት ፡ ስፍራ ፡ አላገኘችም ፥ ወደ ፡ እርሱም ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ተመለሰች ፥ ውኃ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፤ እጁን ፡ ዘረጋና ፡ ተቀበላት ፥ ወደ ፡ እርሱም ፡ ወደ ፡ መር ፲፤ ከብ ፡ ውስጥ ፡ አገባት ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ደግሞ ፡ እስከ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ቆየ ፤ ርግብንም ፡ እንደ ፡ ፲፩፤ ገና ፡ ከመርከብ ፡ ሰደደ ። ርግብም ፡ በማታ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተመለሰች ፤ በአፍዋም ፡ እነሆ ፡ የለመለመ ፡ የወይራ ፡ ቅጠል ፡ ይዛ ፡ ነበር ። ኖኅም ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ ውኃ ፡ እንደ ፡ ቀለለ ፡ ፲፪፤ አወቀ ። ደግሞ ፡ እስከ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ቆየ ፤ ርግብንም ፡ ሰደዳት ፡ ዳግመኛም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አልተመለሰችም ።

፲፫፤ በኖኅ ፡ ዕድሜ ፡ በስድስት ፡ መቶ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ በመጀመሪያው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ውኃው ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ ደረቀ ፤ ኖኅም ፡ የመርከቢቱን ፡ ክዳን ፡ አነሣ ፥ እነሆም ፥ ውኃው ፡ ከምድር ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ደረቀ ፡ አየ ። ፲፬፤ በሁለተኛውም ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በሀያ ፡ ሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ምድር ፡ ደረቀች ።

፲፭፤ እግዚአብሔርም ፡ ለኖኅ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ነገ ፲፮፤ ረው ፡— አንተ ፡ ሚስትህንና ፡ ልጆችህን ፡ የልጆችህንም ፡ ሚስቶች ፡ ይዘህ ፡ ከመርከብ ፡ ውጣ ። ፲፯፤ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ያሉትን ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ፥ ሥጋ ፡ ያላቸውን ፡ ሁሉ ፥ ወፎችንና ፡ እንስሶችን ፡ ሁሉ ፥ በምድር ፡ ላይ ፡ የሚንቀሳቀሱትንም ፡ ሁሉ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አውጣቸው ፤ በምድር ፡ ላይ ፡ ይርመስመሱ ፥ ይዋለዱ ፥ በምድርም ፡ ላይ ፡ ይብዙ ። ፲፰፤ ኖኅም ፡ ልጆቹንና ፡ ሚስቱን ፡ የልጆቹንም ፡ ሚስቶች ፡ ይዞ ፡ ወጣ ፤ አራዊት ፡ ሁሉ ፥ ተንቀሳቃ ፲፱፤ ሾች ፡ ሁሉ ፥ ወፎችም ፡ ሁሉ ፥ በምድር ፡ ላይ ፡ የሚርመሰመሰው ፡ ሁሉ ፡ በየዘመዳቸው ፡ ከመርከብ ፡ ወጡ ።

፳፤ ኖኅም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠውያውን ፡ ሠራ ፥ ከንጹሕም ፡ እንስሳ ፡ ሁሉ ፡ ከንጹሕን ፡ ወፎችም ፡ ሁሉ ፡ ወሰደ ፥ በመሠውያውም ፡ ላይ ፡ ፳፩፤ መሥዋዕትን ፡ አቀረበ ። እግዚአብሔርም ፡ መልካሙን ፡ መዓዛ ፡ አሸተተ ፤ እግዚአብሔርም ፡ በልቡ ፡ አለ ፡— ምድርን ፡ ዳግመኛ ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ አልረግምም ፥ የሰው ፡ ልብ ፡ አሳብ ፡ ከታናሽነቱ ፡ጀምሮ ፡ ክፉ ፡ ነውና ፤ ደግሞም ፡ ከዚህ ፡ ቀድሞ ፡ እንዳደረግሁት ፡ ሕያዋንን ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ፳፪፤ ገና ፡ አልመታም ። በምድር ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ መዝራትና ፡ ማጨድ ፥ ብርድና ፡ሙቀት ፥ በጋና ፡ ክረምት ፥ ቀንና ፡ ሌሊት ፡ አያቋርጡም ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩፤ እግዚአብሔርም ፡ ኖኅንና ፡ ልጆቹን ፡ ባረካቸው ፡ እንዲህም ፡ አላቸው ፡— ብዙ ፡ ተባዙ ፥ ፪፤ ምድርንም ፡ሙሉአት ። አስፈሪነታችሁና ፡ አስደንጋጭነታችሁ ፡ በምድር ፡ አራዊት ፥ በሰማይም ፡ ወፎች ፥ በምድር ፡ ላይ ፡ በሚንቀሳቀሱትም ፥ በባሕር ፡ ዓሦችም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ይሁን ፤ እነርሱም ፡ ፫፤ በእጃችሁ ፡ ተሰጥተዋል ። ሕይወት ፡ ያለው ፡ ተንቀሳቃሽ ፡ ሁሉ ፡ መብል ፡ ይሁናችሁ ፤ ሁሉን ፡ ፬፤ እንደ ፡ ለመለመ ፡ ቡቃያ ፡ ሰጠኋችሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ ነፍሱ ፡ ደሙ ፡ ያለችበትን ፡ ሥጋ ፡ አት ፭፤ ብሉ ፤ ነፍሳችሁ ፡ ያለችበትን ፡ ደማችሁን ፡ በእርግጥ ፡ እሻዋለሁ ፤ ከአራዊት ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ እሻዋለሁ ፤ ከሰውም ፡ እጅ ፥ ከሰው ፡ ወንድም ፡ ፮፤ እጅ ፥ የሰውን ፡ ነፍስ ፡ እሻለሁ ። የሰውን ፡ ደም ፡ የሚያፈስስ ፡ ሁሉ ፡ ደሙ ፡ ይፈስሳል ፤ ሰውን ፡ ፯፤ በእግዚአብሔር ፡ መልክ ፡ ፈጥሮታልና ። እናንተም ፡ ብዙ ፥ ተባዙ ፤ በምድር ፡ ላይ ፡ ተዋለዱ ፥ እርቡባትም ።

፰፤ እግዚአብሔርም ፡ ለኖኅና ፡ ለልጆቹ ፡ እንዲህ ፡ ፱፤ ብሎ ፡ ተናገረ ፡— እኔም ፡ እነሆ ፡ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ ከእናንተና ፡ በኋላ ፡ ከሚመጣው ፡ ከዘራችሁ ፡ ፲፤ ጋር ፡ አቆማለሁ ፤ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ላሉትም ፡ ሕያው ፡ ነፍስ ፡ ላላቸው ፡ ሁሉ ፥ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ከመርከብ ፡ ለወጡት ፡ ለወፎች ፥ ለእንስሳትም ፡ ለምድር ፡ አራዊትም ፡ ሁሉ ፥ ለማንኛውም ፡ ፲፩፤ ለምድር ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ፡ ይሆናል ። ቃል ፡ ኪዳኔንም ፡ ለእናንተ ፡ አቆማለሁ ፤ ሥጋ ፡ ያለውም ፡ ሁሉ ፡ ዳግመኛ ፡ በጥፋት ፡ ውኃ ፡ አይጠፋም ፤ ምድርንም ፡ ለማጥፋት ፡ ዳግመኛ ፡ የጥ ፲፪፤ ፋት ፡ ውኃ ፡ አይሆንም ። እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡— በእኔና ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፥ ከእናንተም ፡ ጋር ፡ ባለው ፡ በሕያው ፡ ነፍስ ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፥ ለዘላለም ፡ የማደርገው ፡ የቃል ፡ ፲፫፤ ኪዳን ፡ ምልክት ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ቀስቴን ፡ በደመና ፡ አድርጌአለሁ ፥ የቃል ፡ ኪዳኑም ፡ ምልክት ፡ ፲፬፤ በእኔና ፡ በምድር ፡ መካከል ፡ ይሆናል ። በም

ድር ፡ ላይ ፡ ደመናን ፡ በጋረድሁ ፡ ጊዜ ፡ ቀስ
፲፬ ቲቱ ፡ በደመናው ፡ ትታያለች ፤ በእኔና ፡ በእና
ንተ ፡ መካከል ፥ ሕያው ፡ ነፍስ ፡ ባለውም ፡
ሥጋ ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ ኪዳ
ኔን ፡ አስባለሁ ፤ ሥጋ ፡ ያለውንም ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋ ፡
ዘንድ ፡ ዳግመኛ ፡ የጥፋት ፡ ውኃ ፡ አይሆንም ።
፲፭ ቀስቲቱም ፡ በደመና ፡ ትሆናለች ፤ በእኔና ፡ በም
ድር ፡ ላይ ፡ በሚኖር ፡ ሥጋ ፡ ባለው ፡ በሕያው ፡
ነፍስ ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ የዘላለም ፡ ቃል ፡
፲፮ ኪዳን ፡ ለማሰብ ፡ አያታለሁ ። እግዚአብሔርም ፡
ኖኅን ፡— በእኔና ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በሚኖር ፡
ሥጋ ፡ ባለው ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ ያቆምሁት ፡
የቃል ፡ ኪዳን ፡ ምልክት ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አለው ።
፲፯ ከመርከብ ፡ የወጡት ፡ የኖኅ ፡ ልጆችም ፡ እነ
ዚህ ፡ ናቸው ፥ ሴም ፥ ካም ፥ ያፌት ፤ ካምም ፡
፲፰ የከነዓን ፡ አባት ፡ ነው ። የኖኅ ፡ ልጆች ፡ እነ
ዚህ ፡ ሦስቱ ፡ ናቸው ፤ ከእነርሱም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡
ተሞላች ።
፳ ኖኅም ፡ ገበሬ ፡ መሆን ፡ ጀመረ ፥ ወይንም ፡
፳፩ ተከለ ። ከወይን ፡ ጠጁም ፡ ጠጣና ፡ ሰከረ ፤
፳፪ በድንኳኑም ፡ ውስጥ ፡ ዕራቁቱን ፡ ሆነ ። የከነ
ዓን ፡ አባት ፡ ካምም ፡ የአባቱን ፡ ዕራቁትነት ፡
አየ ፥ ወደ ፡ ውጭም ፡ ወጥቶ ፡ ለሁለቱ ፡ ወንድ
፳፫ ሞቹ ፡ ነገራቸው ። ሴምና ፡ ያፌትም ፡ ሸማ ፡
ወስደው ፡ በጫንቃቸው ፡ ላይ ፡ አደረጉ ፥ የኋ
ሊትም ፡ ሄደው ፡ የአባታቸውን ፡ ዕራቁትነት ፡
አለበሱ ፤ ፊታቸውም ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ነበረ ፥ የአ
፳፬ ባታቸውንም ፡ ዕራቁትነት ፡ አላዩም ። ኖኅም ፡
ከወይን ፡ ጠጁ ፡ ስካር ፡ ነቃ ፥ ታናሹ ፡ ልጁ ፡
ያደረገበትንም ፡ አወቀ ።
፳፭ እንዲህም ፡ አለ ፡— ከነዓን ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፤
ለወንድሞቹም ፡ የባሪያዎች ፡ ባሪያ ፡ ይሁን ።
፳፮ እንዲህም ፡ አለ ፡— የሴም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ይባረክ ፥ ከነዓንም ፡ ለእነርሱ ፡ ባሪያ ፡
፳፯ ይሁን ። እግዚአብሔርም ፡ ያፌትን ፡ ያስፋ ፥
በሴምም ፡ ድንኳን ፡ ይደር ፤ ከነዓንም ፡ ለእነ
ርሱ ፡ ባሪያ ፡ ይሁን ።
፳፰ ኖኅም ፡ ከጥፋት ፡ ውኃ ፡ በኋላ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡
፳፱ አምሳ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ። ኖኅም ፡ የኖረበት ፡ ዘመን ፡
ሁሉ ፡ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ሞተም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ የኖኅ ፡ ልጆች ፡ የሴም ፡ የካም ፡ የያፌት ፡ ትው
ልድ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ከጥፋት ፡ ውኃም ፡ በኋላ ፡
ልጆች ፡ ተወለዱላቸው ።
፪ የያፌት ፡ ልጆች ፡ ጋሜር ፥ ማጎግ ፥ ማዴ ፥
ያዋን ፥ ይልሳ ፥ ቶቤል ፥ሞሳሕ ፥ ቴራስ ፡ ናቸው ።
፫ የጋሜርም ፡ ልጆች ፡ አስከናዝ ፥ ሪፋት ፥ ቴር
፬ ጋማ ፡ ናቸው ። የያዋንም ፡ ልጆች ፡ ኤሊሳ ፥ ተር
፭ ሴስ ፥ ኪቲም ፥ ሮድኢ ፡ ናቸው ። ከእነዚህም ፡
የአሕዛብ ፡ ደሴቶች ፡ ሁሉ ፡ በየምድራቸው ፡
በየቋንቋቸው ፡ በየነገዳቸው ፡ በየሕዝባቸው ፡
ተከፋፈሉ ።
፮ የካምም ፡ ልጆች ፡ ኩሽ ፥ ምጽራይም ፥ ፋጥ ፥
ከነዓን ፡ ናቸው ። የኩሽም ፡ ልጆች ፡ ሳባ ፥ ኤው
፯ ላጥ ፥ ሰብታ ፥ ራዕማ ፥ ሰበቃታ ፡ ናቸው ። የራ
ዕማ ፡ ልጆችም ፡ ሳባ ፥ ድዳን ፡ ናቸው ። ኩሽም ፡
፰ ናምሩድን ፡ ወለደ ፤ እርሱም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡
ኃያል ፡ መሆንን ፡ ጀመረ ። እርሱም ፡ በእግዚ
፱ አብሔር ፡ ፊት ፡ ኃያል ፡ አዳኝ ፡ ነበረ ፤ ስለዚ
ህም ፡— በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ኃያል ፡ አዳኝ ፡
እንደ ፡ ናምሩድ ፡ ተባለ ። የግዛቱም ፡ መጀመ
፲ ሪያ ፡ በሰናዖር ፡ አገር ፡ ባቢሎን ፥ኦሬክ ፥ አር
ካድ ፥ ካልኔ ፡ ናቸው ። አሦርም ፡ ከዚያች ፡
፲፩ አገር ፡ ወጣ ፤ ነነዌን ፥ የረሆቦትን ፡ ከተማ ፥ ካለ
ህን ፥ በነነዌና ፡ በካለህ ፡ መካከልም ፡ ሬሴንን ፡
፲፪ ሠራ ፤ እርስዋም ፡ ታላቂቱ ፡ ከተማ ፡ ናት ።
፲፫ ምጽራይምም ፡ ሉዲምን ፥ ዐናሚምን ፥ ላህቢ
፲፬ ምን ፥ ነፍታሌምን ፥ ፈትሩሲምን ፥ ከእነርሱ ፡
የፍልስጥኤም ፡ ሰዎች ፡ የወጡባቸውን ፡ ከስ
ሉሂምን ፥ ቀፍቶሪምንም ፡ ወለደ ።
፲፭ ከነዓንም ፡ የበኵር ፡ ልጁን ፡ ሲዶንን ፥ ኬጢ
፲፮ ያውያንንም ፥ ኢያቡሳውያንንም ፥ አሞራውያ
፲፯ ንንም ፥ ጌርጌሳውያንንም ፥ ኤዊያውያንንም ፥
፲፰ ዐሩኬዎንንም ፥ ሲኒንም ፥ አራዴዎንንም ፥ሰማሪ
ዎንንም ፥ አማቴንም ፡ ወለደ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡
፲፱ የከነዓናውያን ፡ ነገድ ፡ ተበተኑ ። የከነዓናው
ያንም ፡ ወሰን ፡ ከሲዶን ፡ አንሥቶ ፡ ወደ ፡ ጌራራ ፡
በኩል ፡ ሲል ፡ እስከ ፡ ጋዛ ፡ ድረስ ፡ ነው ፤ ወደ ፡
ሰዶምና ፡ ወደ ፡ ገሞራ ፥ ወደ ፡ አዳማና ፡ ወደ ፡
ሰቦይም ፡ በኩልም ፡ ሲል ፡ እስከ ፡ ላሣ ፡ ድረስ ፡
፳ ነው ። የካም ፡ ልጆች ፡ በየነገዳቸውና ፡ በየቋ
ንቋቸው ፥ በየምድራቸውና ፡ በየሕዝባቸው ፡
እነዚህ ፡ ናቸው ።
፳፩ ለሴምም ፡ ደግሞ ፡ ልጆች ፡ ተወለዱለት ፤ እር
ሱም ፡ የያፌት ፡ ታላቅ ፡ ወንድምና ፡ የዔቦር ፡
፳፪ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ አባት ፡ የሆነ ፡ ነው ። የሴምም ፡
ልጆች ፡ ኤላም ፥ አሦር ፥ አርፋክስድ ፥ ሉድ ፥
፳፫ አራም ፡ ናቸው ። የአራምም ፡ ልጆች ፡ ዑፅ ፥
፳፬ ሁል ፥ ጌቴር ፥ ሞሶሕ ፡ ናቸው ። አርፋክስ
ድም ፡ ቃይንምን ፡ ወለደ ፤ ቃይንምም ፡ ሳላን ፥
፳፭ ሳላም ፡ ዔቦርን ፡ ወለደ ። ለዔቦርም ፡ ሁለት ፡
ልጆች ፡ ተወለዱለት ፤ የአንደኛው ፡ ስሙ ፡
ፋሌቅ ፡ ነው ፥ ምድር ፡ በዘመኑ ፡ ተከፍላለችና ፤
፳፮ የወንድሙም ፡ ስም ፡ ዮቅጣን ፡ ነው ። ዮቅጣ
ንም ፡ ኤልሞዳድን ፥ ሣሌፍንም ፥ ሐስረሞት
፳፯ ንም ፥ ያራሕንም ፥ ሀዶራምንም ፥ አውዛል
፳፰ ንም ፥ ደቅላንም ፥ ዖባልንም ፥ አቢማኤልንም ፥
፳፱ ሳባንም ፥ አፊርንም ፥ ኤውላጥንም ፥ ዮባብንም ፡
ወለደ ፤ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የዮቅጣን ፡ ልጆች ፡ ናቸው ።
፴ ስፍራቸውም ፡ ከማሴ ፡ አንሥቶ ፡ ወደ ፡ ስፋር ፡
ሲል ፡ እስከ ፡ ምሥራቅ ፡ ተራራ ፡ ድረስ ፡ ነው ።
፴፩ የሴም ፡ ልጆች ፡ በየነገዳቸውና ፡ በየቋንቋቸው ፥
በየምድራቸውና ፡ በየሕዝባቸው ፡ እነዚህ ፡
ናቸው ።
፴፪ የኖኅ ፡ የልጆቹ ፡ ነገዶች ፡ እንደ ፡ ትውልዳ
ቸው ፡ በየሕዝባቸው ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። አሕዛ
ብም ፡ ከጥፋት ፡ ውኃ ፡ በኋላ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡

ከእነዚህ ፡ ተከፋፈሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ምድርም ፡ ሁሉ ፡ በአንድ ፡ ቋንቋና ፡ በአንድ ፡ ንግግር ፡ ነበረች ። ፪ ከምሥራቅም ፡ ተነሥተው ፡ በሄዱ ፡ ጊዜ ፡ በሰናዖር ፡ ምድር ፡ አንድ ፡ ሜዳ ፡ አገኙ ፤ በዚያም ፡ ተቀመጡ ። ፫ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡— ኑ ፥ ጡብ ፡ እንሥራ ፥ በእሳትም ፡ እንተኵሰው ፡ ተባባሉ ። ጡቡም ፡ እንደ ፡ ድንጋይ ፡ ሆነላቸው ፤ የምድርም ፡ ዝፍት ፡ እንደ ፡ ጭቃ ፡ ሆነችላቸው ። ፬ እንዲህም ፡— ኑ ፡ ለእኛ ፡ ከተማና ፡ ራሱ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ የሚደርስ ፡ ግንብ ፡ እንሥራ ፤ በምድር ፡ ላይ ፡ ሳንበተንም ፡ ስማችንን ፡ እናስጠራው ፡ አሉ ። ፭ እግዚአብሔርም ፡ የአዳም ፡ ልጆች ፡ የሠሩትን ፡ ከተማና ፡ ግንብ ፡ ለማየት ፡ ወረደ ። ፮ እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡— እነሆ ፥ እነርሱ ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ናቸው ፥ ለሁሉም ፡ አንድ ፡ ቋንቋ ፡ አላቸው ፤ ይህንም ፡ ለማድረግ ፡ ጀመሩ ፤ አሁንም ፡ ያሰቡትን ፡ ሁሉ ፡ ለመሥራት ፡ አይከለከሉም ። ፯ ኑ ፥ እንውረድ ፤ አንዱ ፡ የአንዱን ፡ ነገር ፡ እንዳይሰማው ፡ ቋንቋቸውን ፡ በዚያ ፡ እንደባልቀው ። ፰ እግዚአብሔርም ፡ ከዚያ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በተናቸው ፤ ከተማይቱንም ፡ መሥራት ፡ ተዉ ። ፱ ስለዚህም ፡ ስምዋ ፡ ባቢሎን ፡ ተባለ ፥ እግዚአብሔር ፡ በዚያ ፡ የምድርን ፡ ቋንቋ ፡ ሁሉ ፡ ደባልቋልና ፤ ከዚያም ፡ እግዚአብሔር ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እነርሱን ፡ በትኖአቸዋል ።

፲ የሴም ፡ ትውልድ ፡ ይህ ፡ ነው ። ሴም ፡ የመቶ ፡ ዓመት ፡ ሰው ፡ ነበረ ፥ አርፋክስድንም ፡ ከጥፋት ፡ ውኃ ፡ በኋላ ፡ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ ወለደ ። ፲፩ ሴምም ፡ አርፋክስድን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ፤ ሞተም ።

፲፪ አርፋክስድም ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ቃይንምንም ፡ ወለደ ፤ ፲፫ አርፋክስድም ፡ ቃይንምን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ፤ ሞተም ። ቃይንምም ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ሳላንም ፡ ወለደ ፤ ቃይንምም ፡ ሳላን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ፤ ሞተም ።

፲፬ ሳላም ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ዔቦርንም ፡ ወለደ ፤ ፲፭ ሳላም ፡ ዔቦርን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ፤ ሞተም ።

፲፮ ዔቦርም ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ አራት ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ፋሌቅንም ፡ ወለደ ፤ ፲፯ ዔቦርም ፡ ፋሌቅን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ፤ ሞተም ።

፲፰ ፋሌቅም ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ራግውንም ፡ ወለደ ፤ ፲፱ ራግውንም ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ ፋሌቅ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ዘጠኝ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ፤ ሞተም ።

፳ ራግውም ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ሴሮሕንም ፡ ወለደ ፤ ፳፩ ራግውም ፡ ሴሮሕን ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ፤ ሞተም ።

፳፪ ሴሮሕም ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ናኮርንም ፡ ወለደ ፤ ፳፫ ናኮርንም ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ ሴሮሕ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ፤ ሞተም ።

፳፬ ናኮርም ፡ መቶ ፡ ዘጠኝ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ታራንም ፡ ወለደ ፤ ፳፭ ታራንም ፡ ከወለደ ፡ በኋላ ፡ ናኮር ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ዘጠኝ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ወለደ ፤ ሞተም ።

፳፮ ታራም ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ አብራምንና ፡ ናኮርን ፡ ሐራንንም ፡ ወለደ ።

፳፯ የታራም ፡ ትውልድ ፡ እነሆ ፡ ይህ ፡ ነው ። ታራ ፡ አብራምንና ፡ ናኮርን ፡ ሐራንንም ፡ ወለደ ፤ ሐራንም ፡ ሎጥን ፡ ወለደ ። ፳፰ ሐራንም ፡ በተወለደበት ፡ አገር ፡ በከለዳውያን ፡ ዑር ፡ በአባቱ ፡ በታራ ፡ ፊት ፡ ሞተ ። ፳፱ አብራምና ፡ ናኮርም ፡ ሚስቶችን ፡ አገቡ ፤ የአብራም ፡ ሚስት ፡ ስምዋ ፡ ሦራ ፡ ነው ፤ የናኮር ፡ ሚስት ፡ የሐራን ፡ ልጅ ፡ ሚልካ ፡ ናት ፤ ሐራንም ፡ የሚልካና ፡ የዮስካ ፡ አባት ፡ ነው ። ፴ ሦራም ፡ መካን ፡ ነበረች ፤ ልጅ ፡ አልነበራትም ። ፴፩ ታራም ፡ ልጁን ፡ አብራምንና ፡ የልጅ ፡ ልጁን ፡ የሐራንን ፡ ልጅ ፡ ሎጥን ፡ የልጁንም ፡ የአብራምን ፡ ሚስት ፡ ምራቱን ፡ ሦራን ፡ ወሰደ ፤ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ከነዓን ፡ ምድር ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ከከለዳውያን ፡ ዑር ፡ ወጡ ፤ ወደ ፡ ካራንም ፡ መጡ ፥ ከዚያም ፡ ተቀመጡ ። ፴፪ የታራም ፡ ዕድሜ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፤ ታራም ፡ በካራን ፡ ሞተ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ አብራምን ፡ አለው ፡— ከአገርህ ፡ ከዘመዶችህም ፡ ከአባትህም ፡ ቤት ፡ ተለይተህ ፡ እኔ ፡ ወደማሳይህ ፡ ምድር ፡ ውጣ ። ፪ ታላቅ ፡ ሕዝብም ፡ አደርግሃለሁ ፥ እባርክሃለሁ ፥ ስምህንም ፡ አከብረዋለሁ ፤ ለበረከትም ፡ ሁን ፤ ፫ የሚባርኩህንም ፡ እባርካለሁ ፥ የሚረግሙህንም ፡ እረግማለሁ ፤ የምድር ፡ ነገዶችም ፡ ሁሉ ፡ በአንተ ፡ ይባረካሉ ። ፬ አብራምም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ነገረው ፡ ሄደ ፤ ሎጥም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሄደ ፤ አብራምም ፡ ከካራን ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ የሰባ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ሰው ፡ ነበረ ። ፭ አብራምም ፡ ሚስቱን ፡ ሦራንና ፡ የወንድሙን ፡ ልጅ ፡ ሎጥን ፥ ያገኙትን ፡ ከብት ፡ ሁሉና ፡ በካራን ፡ ያገኙአቸውን ፡ ሰዎች ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ከነዓን ፡ ምድር ፡ ለመሄድ ፡ ወጣ ፤ ወደ ፡ ከነዓንም ፡ ምድር ፡ ገቡ ። ፮ አብራምም ፡ እስከ ፡ ሴኬም ፡ ስፍራ ፡ እስከ ፡ ሞሬ ፡ የአድባር ፡ ዛፍ ፡ ድረስ ፡ በምድር ፡ አለፈ ፤ የከነዓን ፡ ሰዎችም ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በምድሩ ፡ ነበሩ ። ፯ እግዚአብሔርም ፡ ለአብራም ፡ ተገለጠለትና ፡— ይህችን ፡ ምድር ፡ ለዘርህ ፡ እሰጣለሁ ፡

አለው ። እርሱም ፡ ለተገለጠለት ፡ ለእግዚአብ
፰ ሔር ፡ በዚያ ፡ ስፍራ ፡ መሠውያን ፡ ሠራ ። ከዚ
ያም ፡ በቤቴል ፡ ምሥራቅ ፡ ወዳለው ፡ ተራራ ፡
ወጣ ፥ በዚያም ፡ ቤቴልን ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡
ጋይን ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ አድርጎ ፡ ድንኳኑን ፡
ተከለ ፤ በዚያም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠውያን ፡
፱ ሠራ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ ጠራ ። አብ
ራምም ፡ ከዚያ ፡ ተነሣ ፥ እየተጓዘም ፡ ወደ ፡
አዜብ ፡ ሄደ ።

፲ በምድርም ፡ ራብ ፡ ሆነ ፤ አብራምም ፡ በዚያ ፡
በእንግድነት ፡ ይቀመጥ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡
፲፩ ወረደ ፥ በምድር ፡ ራብ ፡ ጸንቶ ፡ ነበርና ። ወደ ፡
ግብፅም ፡ ለመግባት ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፡ ሚስቱን ፡
ሦራን ፡ እንዲህ ፡ አላት ፡— አንቺ ፡ መልከ ፡ መል
ካም ፡ ሴት ፡ እንደ ፡ ሆንሽ ፡ እነሆ ፡ እኔ ፡ አውቃ
፲፪ ለሁ ፤ የግብፅ ፡ ሰዎች ፡ ያዩሽ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡—
ሚስቱ ፡ ናት ፡ ይላሉ ፤ እኔንም ፡ ይገድሉኛል ፥
፲፫ አንቺንም ፡ በሕይወት ፡ ይተዉሻል ። እንግዲህ ፡
በአንቺ ፡ ምክንያት ፡ መልካም ፡ ይሆንልኝ ፡
ዘንድ ፥ ስለ ፡ አንቺም ፡ ነፍሴ ፡ ትድን ፡ ዘንድ ፡—
፲፬ እኅቱ ፡ ነኝ ፡ በዪ ። አብራምም ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡
በገባ ፡ ጊዜ ፡ የግብፅ ፡ ሰዎች ፡ ሴቲቱን ፡ እጅግ ፡
፲፭ ውብ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ አዩ ፤ የፈርዖንም ፡ አለ
ቆች ፡ አዩአት ፥ በፈርዖንም ፡ ፊት ፡ አመሰገኑ
አት ፤ ሴቲቱንም ፡ ወደ ፡ ፈርዖን ፡ ቤት ፡ ወሰዱ
፲፮ አት ። ለአብራምም ፡ ስለ ፡ እርስዋ ፡ መልካም ፡
አደረገለት ፤ ለእርሱ ፡ በጎችም ፡ በሬዎችም ፡
አህዮችም ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ባሪያዎችም ፡
፲፯ ግመሎችም ፡ ነበሩት ። እግዚአብሔርም ፡ በአ
ብራም ፡ ሚስት ፡ በሦራ ፡ ምክንያት ፡ ፈርዖን
ንና ፡ የቤቱን ፡ ሰዎች ፡ በታላቅ ፡ መቅሠፍት ፡
፲፰ መታ ። ፈርዖንም ፡ አብራምን ፡ ጠርቶ ፡
አለው ፡— ይህ ፡ ያደረግህብኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
እርስዋ ፡ ሚስትህ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ ለምን ፡ አል
፲፱ ገለጥህልኝም ? ለምንስ ፡— እኅቴ ፡ ናት ፡ አልህ ?
እኔ ፡ ሚስት ፡ ላደርጋት ፡ ወስጀአት ፡ ነበር ።
አሁንም ፡ ሚስትህ ፡ እነኋት ፤ ይዘሃት ፡ ሂድ ።
፳ ፈርዖንም ፡ ሰዎቹን ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ አዘዘ ፥ እር
ሱንም ፡ ሚስቱንም ፡ ከብቱንም ፡ ሁሉ ፡ሸኙአ
ቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ አብራምም ፡ ከግብፅ ፡ ወጣ ፤ እርሱና ፤ ሚስቱ ፡
ለእርሱ ፡ የነበረውም ፡ ሁሉ ፡ ሎጥም ፡ ከእርሱ ፡
፪ ጋር ፡ ወደ ፡ አዜብ ፡ ወጡ ። አብራምም ፡ በከ
፫ ብት ፡ በብርና ፡ በወርቅ ፡ እጅግ ፡ በለጠገ ። ከአ
ዜብ ፡ ባደረገው ፡ በጕዞውም ፡ ወደ ፡ ቤቴል ፡
በኩል ፡ ሄደ ፤ ያም ፡ ስፍራ ፡ አስቀድሞ ፡ በቤ
ቴልና ፡ በጋይ ፡ መካከል ፡ ድንኳን ፡ ተክሎበት ፡
፬ የነበረው ፡ ነው ፤ ያም ፡ ስፍራ ፡ አስቀድሞ ፡
መሠውያ ፡ የሠራበት ፡ ነው ፤ በዚያም ፡ አብ
፭ ራም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ጠራ ። ከአብ
ራም ፡ ጋር ፡ የሄደው ፡ ሎጥ ፡ ደግሞ ፡ የላምና ፡
፮ የበግ ፡ መንጋ ፡ ድንኳንም ፡ ነበረው ። በአንድ
ነትም ፡ ይቀመጡ ፡ ዘንድ ፡ ምድር ፡ አልበቃቸ
ውም ፤ የነበራቸው ፡ እጅግ ፡ ነበረና ፡ በአንድ
፯ ነት ፡ ሊቀመጡ ፡ አልቻሉም ። የአብራምንና ፡
የሎጥን ፡ መንጎች ፡ በሚጠብቁት ፡ መካከልም ፡
ጠብ ፡ ሆነ ፤ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ከነዓናውያንና ፡
ፌርዛውያን ፡ በዚያች ፡ ምድር ፡ ተቀምጠው ፡
፰ ነበር ። አብራምም ፡ ሎጥን ፡ አለው ፡— እኛ ፡
ወንድማማች ፡ ነንና ፡ በእኔና ፡ በአንተ ፡ በእረኞ
ቼና ፡ በእረኞችህ ፡ መካከል ፡ ጠብ ፡ እንዳይሆን ፡
፱ እለምንሃለሁ ። ምድር ፡ ሁሉ ፡ በፊትህ ፡ አይደለ
ችምን ? ከእኔ ፡ ትለይ ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ፤
አንተ ፡ ግራውን ፡ ብትወስድ ፡ እኔ ፡ ወደ ፡ ቀኝ ፡
እሄዳለሁ ፤ አንተም ፡ ቀኙን ፡ ብትወስድ ፡ እኔ ፡
፲ ወደ ፡ ግራ ፡ እሄዳለሁ ። ሎጥም ፡ ዓይኑን ፡ አነሣ ፥
በዮርዳኖስ ፡ ዙሪያ ፡ ያለውንም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡
ውኃ ፡ የሞላበት ፡ መሆኑን ፡ አየ ፤ እግዚአብ
ሔር ፡ ሰዶምንና ፡ ገሞራን ፡ ከማጥፋቱ ፡ አስቀ
ድሞ ፡ እስከ ፡ ዞዓር ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ገነት ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ አምሳል ፡ ነበረ ።
፲፩ ሎጥም ፡ በዮርዳኖስ ፡ ዙሪያ ፡ ያለውን ፡ አገር ፡
ሁሉ ፡ መረጠ ፤ ሎጥም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡
ተጓዘ ፤ አንዱም ፡ ከሌላው ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡
፲፪ ተለያዩ ። አብራም ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ተቀ
መጠ ፡ ሎጥም ፡ በአገሩ ፡ ሜዳ ፡ ባሉት ፡ ከተ
ሞች ፡ ተቀመጠ ፥ እስከ ፡ ሰዶምም ፡ ድረስ ፡
፲፫ ድንኳኑን ፡ አዘዋወረ ። የሰዶም ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡
ክፉዎችና ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እጅግ ፡ ኃጢ
አተኞች ፡ ነበሩ ።

፲፬ ሎጥ ፡ ከተለየው ፡ በኋላም ፡ እግዚአብሔር ፡
አብራምን ፡ አለው ፡— ዓይንህን ፡ አንሣና ፡ አንተ ፡
ካለህበት ፡ ስፍራ ፡ ወደ ፡ ሰሜንና ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡
፲፭ ወደ ፡ ምሥራቅና ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ እይ ፤ የም
ታያትን ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ለአንተና ፡ ለዘርህ ፡ ለዘ
፲፮ ላለም ፡ እሰጣለሁና ። ዘርህንም ፡ እንደ ፡ ምድር ፡
አሸዋ ፡ አደርጋለሁ ፤ የምድርን ፡ አሸዋን ፡ ይቈ
ጥር ፡ ዘንድ ፡ የሚችል ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ዘርህ ፡
፲፯ ደግሞ ፡ ይቈጠራል ። ተነሣ ፡ በምድር ፡ በርዝ
መትዋም ፡ በስፋትዋም ፡ ሂድ ፤ እርስዋን ፡ ለአ
፲፰ ንተ ፡ እሰጣለሁና ። አብራምም ፡ ድንኳኑን ፡
ነቀለ ፡ መጥቶም ፡ በኬብሮን ፡ ባለው ፡ በመምሬ ፡
የአድባር ፡ ዛፍ ፡ ተቀመጠ ፤ በዚያም ፡ ለእግዚ
አብሔር ፡ መሠውያን ፡ ሠራ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ በሰናዖር ፡ ንጉሥ ፡ በአምራፌል ፥ በእላሳር ፡
ንጉሥ ፡ በአርዮክ ፥ በኤላም ፡ ንጉሥ ፡ በኮሎ
ዶጎምር ፥ በአሕዛብ ፡ ንጉሥ ፡ በቲድዓል ፡ ዘመን ፡
፪ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ ከሰዶም ፡ ንጉሥ ፡ ከባላ ፥ ከገሞራ ፡
ንጉሥ ፡ ከብርሳ ፥ ከአዳማ ፡ ንጉሥ ፡ ከሰነአብ ፥
ከሰቦይም ፡ ንጉሥ ፡ ከሰሜበር ፥ ዞዓር ፡ ከተባ
ለች ፡ ከቤላ ፡ ንጉሥም ፡ ጋር ፡ ሰልፍ ፡ አደረጉ ።
፫ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ በሲዲም ፡ ሸለቆ ፡ ተሰብስበው ፡
ተባበሩ ፤ ይኸውም ፡ የጨው ፡ ባሕር ፡ ነው ።
፬ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ለኮሎዶጎምር ፡ ተገዝ

ተው ፡ ነበር ፥ በአሥራ ፡ ሦስተኛውም ፡ ዓመት ፡
፭ ፤ ዐመፁ ። በአሥራ ፡ አራተኛውም ፡ ዓመት ፡
ከሎዶጎምርና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ ነገሥ
ታት ፡ መጡ ፤ ራፋይምን ፡ በአስጣሮት ፡ ቃርና
ይም ፥ ዙዚምንም ፡ በሃም ፥ ኤሚምንም ፡
፮ ፤ በሴዊ ፡ ቂርያታይም ፡ መቱ ፤ የሖር ፡ ሰዎች
ንም ፡ በሴይር ፡ ተራራቸው ፡ በበረሀ ፡ አጠገብ ፡
እስካለች ፡ እስከ ፡ ኤል ፡ ፋራን ፡ ድረስ ፡ መቱ ።
፯ ፤ ተመልሰውም ፡ ቃዴስ ፡ ወደ ፡ ተባለች ፡ ወደ ፡
ዓይንሚስፓጥ ፡ መጡ ፤ የአማሌቅን ፡ አገር ፡
ሁሉና ፡ ደግሞ ፡ በሐሴሶን ፡ ታማር ፡ የነበረውን ፡
፰ ፤ አሞራውያንን ፡ መቱ ። የሰዶም ፡ ንጉሥና ፡
የገሞራ ፡ ንጉሥ ፥ የአዳማ ፡ ንጉሥና ፡ የሰቦ
ይም ፡ ንጉሥ ፥ ዘዓር ፡ የተባለች ፡ የቤላ ፡ ንጉ
ሥም ፡ ወጡ ፤ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ በሲዲም ፡ ሸለቆ ፡
፱ ፤ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ለሰልፍ ፡ ወጡ ፤ የኤላምን ፡
ንጉሥ ፡ ከሎዶጎምርን ፥ የአሕዛብን ፡ ንጉሥ ፡
ቲድዓልን ፥ የሰናዖርን ፡ ንጉሥ ፡ አምራፌልን ፥
የእላሳርን ፡ ንጉሥ ፡ አርዮክን ፡ ለመውጋት ፡
አምስቱ ፡ ነገሥታት ፡ በእነዚህ ፡ በአራቱ ፡ ላይ ፡
፲ ፤ ወጡ ። በሲዲም ፡ ሸለቆ ፡ ግን ፡ የዝፍት ፡ ጕድ
ጓዶች ፡ ነበሩበት ። የሰዶም ፡ ንጉሥ ፡ የገሞራ ፡
ንጉሥም ፡ ሸሹና ፡ ወደዚያ ፡ ወደቁ ፤ የቀሩ
፲፩ ፤ ትም ፡ ወደ ፡ ተራራ ፡ ሸሹ ። የሰዶምንና ፡ የገ
ሞራን ፡ ከብት ፡ ሁሉ ፡ መብላቸውንም ፡ ሁሉ ፡
፲፪ ፤ ወስደው ፡ ሄዱ ። በሰዶም ፡ ይኖር ፡ የነበረውን ፡
የአብራምን ፡ የወንድም ፡ ልጅ ፡ ሎጥን ፡ ደግሞ ፡
ከብቱንም ፡ ወስደው ፡ ሄዱ ።
፲፫ ፤ አንድ ፡ የሸሸ ፡ ሰውም ፡ መጣ ፥ ለዕብራዊው ፡
ለአብራምም ፡ ነገረው ፤ እርሱም ፡ የኤስኮል ፡
ወንድምና ፡ የአውናን ፡ ወንድም ፡ በሆነ ፡ በአሞ
ራዊ ፡ መምሬ ፡ የአድባር ፡ ዛፍ ፡ ይኖር ፡ ነበር ፤
እነዚያም ፡ ከአብራም ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
፲፬ ፤ ገብተው ፡ ነበር ። አብራምም ፡ ወንድሙ ፡
እንደ ፡ ተማረከ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ በቤቱ ፡ የተወለ
ዱትን ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ አሥራ ፡ ስምንት ፡ ብላ
ቴኖቹን ፡ አሰለፈ ፥ ፍለጋቸውንም ፡ ተከትሎ ፡
፲፭ ፤ እስከ ፡ ዳን ፡ ድረስ ፡ ሄደ ። ብላቴኖቹንም ፡
ከፍሎ ፡ በሌሊት ፡ እርሱ ፡ ከባሪያዎቹ ፡ ጋር ፡
ወረደባቸው ፥ መታቸውም ፥ በደማስቆ ፡ ግራ ፡
እስካለችውም ፡ እስከ ፡ ሖባ ፡ ድረስ ፡ አሳደ
፲፮ ፤ ዳቸው ። ከብቱንም ፡ ሁሉ ፡ አስመለሰ ፥ ደግ
ሞም ፡ ወንድሙን ፡ ሎጥንና ፡ ከብቶቹን ፡ ሴቶ
ችንና ፡ ሕዝቡን ፡ ደግሞ ፡ መለሰ ።
፲፯ ፤ ከሎዶጎምርንና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩትን ፡
ነገሥታት ፡ ወግቶ ፡ ከተመለሰ ፡ በኋላም ፡ የሰ
ዶም ፡ ንጉሥ ፡ የንጉሥ ፡ ሸለቆ ፡ በሆነ ፡ በሴዊ ፡
፲፰ ፤ ሸለቆ ፡ ሊቀበለው ፡ ወጣ ። የሳሌም ፡ ንጉሥ ፡
መልከ ፡ ጼዴቅም ፡ እንጀራንና ፡ የወይን ፡ ጠጅን ፡
አወጣ ፤ እርሱም ፡ የልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡
፲፱ ፤ ካህን ፡ ነበረ ። ባረከውም ፡— አብራም ፡ ሰማ
ይንና ፡ ምድርን ፡ ለሚገዛ ፡ ለልዑል ፡ እግዚአ
፳ ፤ ብሔር ፡ የተባረከ ፡ ነው ፤ ጠላቶችህን ፡ በእ
ጅህ ፡ የጣለልህ ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔርም ፡ የተ
ባረከ ፡ ነው ፡ አለውም ። አብራምም ፡ ከሁሉ ፡
አሥራትን ፡ ሰጠው ። የሰዶም ፡ ንጉሥም ፡ ፳፩ ፤
አብራምን ፡— ሰዎቹን ፡ ስጠኝ ፥ ከብቱን ፡ ግን ፡
ለአንተ ፡ ውሰድ ፡ አለው ። አብራምም ፡ የሰ ፳፪ ፤
ዶምን ፡ ንጉሥ ፡ አለው ፡— ሰማይንና ፡ ምድርን ፡
ወደሚገዛ ፡ ወደ ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ እጄን ፡
ከፍ ፡ አድርጌአለሁ ፤ አንተ ፡— አብራምን ፡ ባለ ፳፫፡፳፬፡
ጠጋ ፡ አደረግሁት ፡ እንዳትል ፥ ብላቴኖቹ ፡ ከበ
ሉት ፡ በቀር ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ከሄዱትም ፡ ድርሻ ፡
በቀር ፥ ፈትልም ፡ ቢሆን ፡ የጫማ ፡ ማዘቢያም ፡
ቢሆን ፥ ለአንተ ፡ ከሆነው ፡ ሁሉ ፡ እንዳልወስድ ፤
አውናን ፡ ኤስኮልም ፡ መምሬም ፡ እነርሱ ፡ ድር
ሻቸውን ፡ ይውሰዱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ ፤ ከዚህ ፡ ነገር ፡ በኋላም ፡ የእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ በራእይ ፡ ወደ ፡ አብራም ፡ መጣ ፥ እን
ዲህ ፡ሲል ፡— አብራም ፡ ሆይ ፥ አትፍራ ፤ እኔ ፡
ለአንተ ፡ ጋሻህ ፡ ነኝ ፤ ዋጋህም ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡
፪ ፤ ነው ። አብራምም ፡— አቤቱ ፡ እግዚአብሔር ፡
ሆይ ፥ ምንን ፡ ትሰጠኛለህ ? እኔም ፡ ያለ ፡ ልጅ ፡
እሄዳለሁ ፤ የቤቴም ፡ መጋቢ ፡ የደማስቆ ፡ ሰው ፡
፫ ፤ ይህ ፡ ኤሊዔዘር ፡ ነው ፡ አለ ። አብራምም ፡—
ለእኔ ፡ ዘር ፡ አልሰጠኸኝም ፤ እነሆም ፥ በቤቴ ፡
፬ ፤ የተወለደ ፡ ሰው ፡ ይወርሰኛል ፡ አለ ። እነሆም ፥
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ
ለት ፡— ይህ ፡ አይወርስህም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከጉ
፭ ፤ ልበትህ ፡ የሚወጣው ፡ ይወርስሃል ። ወደ ፡
ሜዳም ፡ አወጣውና ፡— ወደ ፡ ሰማይ ፡ ተመል
ከት ፥ ከዋክብትንም ፡ ልትቈጥራቸው ፡ ትችል ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ ቍጠር ፡ አለው ። ዘርህም ፡ እን
፮ ፤ ደዚሁ ፡ ይሆናል ፡ አለው ። አብራምም ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ አመነ ፥ ጽድቅም ፡ ሆኖ ፡ ተቈ
፯ ፤ ጠረለት ። ይህችን ፡ ምድር ፡ ትወርሳት ፡ ዘንድ ፡
እንድሰጥህ ፡ ከከለዳውያን ፡ ዑር ፡ ያወጣሁህ ፡
፰ ፤ እግዚአብሔር ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ አለው ። አቤቱ ፡
እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ እንድወርሳት ፡ በምን ፡
፱ ፤ አውቃለሁ ? አለ ። እርሱም ፡— የሦስት ፡
ዓመት ፡ ጊደር ፥ የሦስት ፡ ዓመት ፡ ፍየልም ፥
የሦስት ፡ ዓመት ፡ በግም ፥ ዋኖስም ፥ ርግብም ፡
፲ ፤ ያዝልኝ ፡ አለው ። እነዚህንም ፡ ሁሉ ፡ ወሰደ
ለት ፥ በየሁለትም ፡ ከፈላቸው ፥ የተከፈሉት
ንም ፡ በየወገኑ ፡ ትይዩ ፡ አደረጋቸው ፤ ወፎ
፲፩ ፤ ችን ፡ ግን ፡ አልከፈለም ። አሞራዎችም ፡ በሥ
ጋው ፡ ላይ ፡ ወረዱ ፥ አብራምም ፡ አበረራቸው ።
፲፪ ፤ ፀሐይም ፡ በገባች ፡ ጊዜ ፡ በአብራም ፡ ከባድ ፡
እንቅልፍ ፡ መጣበት ፤ እነሆም ፥ ድንጋጤና ፡
፲፫ ፤ ታላቅ ፡ ጨለማ ፡ ወደቀበት ፤ አብራምንም ፡
አለው ፡— ዘርህ ፡ ለእርሱ ፡ ባልሆነች ፡ ምድር ፡
ስደተኞች ፡ እንዲሆኑ ፡ በእርግጥ ፡ እወቅ ፤ ባሪ
ያዎች ፡ አድርገውም ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡
፲፬ ፤ ያስጨንቋቸዋል ። ደግሞም ፡ በባርነት ፡ በሚ

ቍ. ፪ ፡ ኤሊዔዘር ፡ የተባለውን ፡ የግዕዙ ፡ መጽሐፍ ፡
ኢያውብር ፡ ይለዋል ።

ገዙአቸው ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ እኔ ፡ እፈርዳለሁ ፤ ከዚ
፲፭ ያም ፡ በኋላ ፡ በብዙ ፡ ከብት ፡ ይወጣሉ ። አንተ ፡
ግን ፡ ወደ ፡ አባቶችህ ፡ በሰላም ፡ ትሄዳለህ ፤
፲፮ በመልካም ፡ ሽምግልና ፡ ትቀበራለህ ። በአራ
ተኛው ፡ ትውልድ ፡ ግን ፡ ወደዚህ ፡ ይመለሳሉ ፤
የአሞራውያን ፡ ኃጢአት ፡ ገና ፡ አልተፈጸመ
፲፯ ምና ። ፀሐይም ፡ በገባች ፡ ጊዜ ፡ ታላቅ ፡
ጨለማ ፡ ሆነ ፤ የምድጃ ፡ ጢስና ፡ የእሳት ፡ ነበ
ልባል ፡ በዚያ ፡ በተከፈለው ፡ መካከል ፡ አለፈ ።
፲፰ በዚያ ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአብራም ፡ እን
ዲህ ፡ ብሎ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረገ ፦ ከግብፅ ፡
ወንዝ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ትልቁ ፡ ወንዝ ፡ እስከ ፡
ኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ፡ ይህችን ፡ ምድር ፡
፲፱ ለዘርህ ፡ ሰጥቼአለሁ ፤ ቄናውያንን ፡ ቄኔዛውያ
፳ ንንም ፡ ቀድሞናውያንንም ፡ ኬጢያውያንንም ፡
፳፩ ፌርዛውያንንም ፡ ራፋይምንም ፡ አሞራውያ
ንንም ፡ ከነዓናውያንንም ፡ ጌርጌሳውያንንም ፡
ኢያቡሳውያንንም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ የአብራም ፡ ሚስት ፡ ሦራ ፡ ግን ፡ ለአብራም ፡
ልጅ ፡ አልወለደችለትም ፡ ነበር ፤ ስምዋ ፡ አጋር ፡
፪ የተባለ ፡ ግብፃዊት ፡ ባሪያም ፡ ነበረቻት ። ሦራም ፡
አብራምን ፦ እነሆ ÷ እንዳልወልድ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ዘጋኝ ፤ ምናልባት ፡ ከእርስዋ ፡ በልጅ ፡
እታነጽ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ግባ ፡ አለ
፫ ችው ። አብራምም ፡ የሦራን ፡ ቃል ፡ ሰማ ። አብ
ራምም ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ አሥር ፡ ዓመት ፡
ከተቀመጠ ፡ በኋላ ÷ የአብራም ፡ ሚስት ፡ ሦራ ፡
ግብፃዊት ፡ ባሪያዋን ፡ አጋርን ፡ ወስዳ ፡ ለባልዋ ፡
ለአብራም ፡ ሚስት ፡ ትሆነው ፡ ዘንድ ፡ ሰጠችው ።
፬ እርሱም ፡ ወደ ፡ አጋር ፡ ገባ ÷ አረገዘችም ፤ እን
ዳረገዘችም ፡ ባየች ፡ ጊዜ ፡ እመቤትዋን ፡ በዓይ
፭ ንዋ ፡ አቃለለች ። ሦራም ፡ አብራምን ፦ መገ
ፋቴ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ይሁን ፤ እኔ ፡ ባሪያዬን ፡
በብብትህ ፡ ሰጠሁህ ፤ እንዳረገዘችም ፡ ባየች ፡
ጊዜ ፡ እኔን ፡ በዓይንዋ ፡ አቃለለችኝ ፤ እግዚአ
ብሔር ፡ በእኔና ፡ በአንተ ፡ መካከል ፡ ይፍረድ ፡
፮ አለችው ። አብራምም ፡ ሦራን ፦ እነሆ ፡ ባሪ
ያሽ ፡ በእጅሽ ፡ ናት ፤ እንደ ፡ ወደድሽ ፡ አድርጊ
በት ፡ አላት ። ሦራም ፡ በሠቀየቻት ፡ ጊዜ ፡ አጋር ፡
ከፊትዋ ፡ ኰበለለች ።

፯ የእግዚአብሔር ፡ መልአክም ፡ በውኃ ፡ ምንጭ ፡
አጠገብ ፡ በበረሀ ፡ አገኛት ፤ ምንጩም ፡ ወደ ፡ ሱር ፡
፰ በምትወስደው ፡ መንገድ ፡ አጠገብ ፡ ነው ። እር
ሱም ፦ የሦራ ፡ ባሪያ ፡ አጋር ፡ ሆይ ÷ ከወዴት ፡
መጣሽ ? ወዴትስ ፡ ትሄጃለሽ ? አላት ። እር
ስዋም ፦ እኔ ፡ ከእመቤቴ ፡ ከሦራ ፡ የኰበለልሁ ፡
፱ ነኝ ፡ አለች ። የእግዚአብሔር ፡ መልአክም ፦
ወደ ፡ እመቤትሽ ፡ ተመለሺ ÷ ከእጅዋም ፡ በታች ፡
፲ ሆነሽ ፡ ተገዢ ፡ አላት ። የእግዚአብሔር ፡ መልአ
ክም ፦ ዘርሽን ፡ እጅግ ፡ አበዛለሁ ÷ ከብዛቱም ፡
፲፩ የተነሣ ፡ አይቈጠርም ፡ አላት ። የእግዚአብሔር ፡
መልአክም ፡ አላት ፦ እነሆ ፡ አንቺ ፡ ፀንሰሻል ÷
ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ትወልጃለሽ ፤ ስሙንም ፡ እስ
ማኤል ፡ ብለሽ ፡ ትጠሪዋለሽ ÷ እግዚአብሔር ፡
፲፪ መከራሽን ፡ ሰምቶአልና ። እርሱም ፡ የበዳ ፡
አህያ ፡ የሚመስል ፡ ሰው ፡ ይሆናል ፤ እጁ ፡
በሁሉ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ÷ የሁሉም ፡ እጅ ፡ ደግሞ ፡
በእርሱ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፤ እርሱም ፡ በወንድሞቹ ፡
፲፫ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ይኖራል ። እርስዋም ፡ ይናገራት ፡
የነበረውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ኤልሮኢ ፡
ብላ ፡ ጠራች ፤ የሚያየኝን ፡ በውኑ ፡ እዚህ ፡ ደግሞ ፡
፲፬ አየሁትን ? ብላለችና ። ስለዚህም ፡ የዚያ ፡ ጕድ
ጓድ ፡ ስም ፡ ብኤርለሃይሮኢ ፡ ተብሎ ፡ ተጠራ ፤
እርሱም ፡ በቃዴስና ፡ በባሬድ ፡ መካከል ፡ ነው ።
፲፭ አጋርም ፡ ለአብራም ፡ ወንድ ፡ ልጅን ፡ ወለደ
ችለት ፤ አብራምም ፡ አጋር ፡ የወለደችለትን ፡
የልጁን ፡ ስም ፡ እስማኤል ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።
፲፮ አጋር ፡ እስማኤልን ፡ ለአብራም ፡ በወለደችለት ፡
ጊዜ ፡ አብራም ፡ የሰማንያ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡
ሰው ፡ ነበረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ አብራምም ፡ የዘጠና ፡ ዘጠኝ ፡ ዓመት ፡ ሰው ፡
በሆነ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአብራም ፡ ተገለ
ጠለትና ፦ እኔ ፡ ኤልሻዳይ ፡ ነኝ ፤ በፊቴ ፡ ተመላ
፪ ለስ ÷ ፍጹምም ፡ ሁን ፤ ቃል ፡ ኪዳኔንም ፡ በእኔና ፡
በአንተ ፡ መካከል ፡ አደርጋለሁ ÷ እጅግም ፡ አበዛ
፫ ሃለሁ ፡ አለው ። አብራምም ፡ በግምባሩ ፡ ወደቀ ፤
እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፦
፬ እነሆ ÷ ቃል ፡ ኪዳኔ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነው ፤ ለብዙ ፡
፭ አሕዛብም ፡ አባት ፡ ትሆናለህ ። ከዛሬም ፡ ጀምሮ ፡
እንግዲህ ፡ ስምህ ፡ አብራም ፡ ተብሎ ፡ አይጠራ ÷
ነገር ፡ ግን ፡ ስምህ ፡ አብርሃም ፡ ይሆናል ፤ ለብዙ ፡
፮ አሕዛብ ፡ አባት ፡ አድርጌሃለሁና ። እጅግም ፡
አበዛሃለሁ ÷ ሕዝብም ፡ አደርግሃለሁ ÷ ነገሥታ
፯ ትም ፡ ከአንተ ፡ ይወጣሉ ። ቃል ፡ ኪዳኔንም ፡
በእኔና ፡ በአንተ ፡ መካከል ፡ ከአንተም ፡ በኋላ ፡
ከዘርህ ፡ ጋር ፡ በትውልዳቸው ፡ ለዘላለም ፡ ኪዳን ፡
አቆማለሁ ÷ ለአንተና ፡ ከአንተ ፡ በኋላ ፡ ለዘርህ ፡
፰ አምላክ ፡ እሆን ፡ ዘንድ ። በእንግድነት ፡ የም
ትኖርበትን ፡ ምድር ÷ የከነዓን ፡ ምድር ፡ ሁሉ ÷
ለዘላለም ፡ ግዛት ፡ ይሆንህ ፡ ዘንድ ፡ ለአንተና ፡
ከአንተ ፡ በኋላ ፡ ለዘርህ ፡ እሰጣለሁ ፤ አምላክም ፡
እሆናቸዋለሁ ።

፱ እግዚአብሔርም ፡ አብርሃምን ፡ አለው ፦
አንተ ፡ ደግሞ ፡ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ ትጠብቃለህ ÷
አንተ ፡ ከአንተም ፡ በኋላ ፡ ዘርህ ፡ በትውልዳ
፲ ቸው ። በእኔና ፡ በአንተ ፡ መካከል ÷ ከአንተም ፡
በኋላ ፡ በዘርህ ፡ መካከል ፡ የምትጠብቁት ፡ ቃል ፡
ኪዳኔ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ከእናንተ ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡
፲፩ ይገረዝ ። የቍልፈታችሁንም ፡ ሥጋ ፡ ትገረዛ
ላችሁ ፤ በእኔና ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡ ላለውም ፡
፲፪ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ምልክት ፡ ይሆናል ። የስምንት ፡
ቀን ፡ ልጅ ፡ ይገረዝ ፤ በቤት ፡ የተወለደ ፡ ወይም ፡
ከዘራችሁ ፡ ያይደለ ፡ በብርም ፡ ከእንግዳ ፡ ሰው ፡
የተገዛ ÷ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ በትውልዳችሁ ፡ ይገ

፲፫ ረዝ ። በቤትህ ፡ የተወለደ ፡ በብርህም ፡ የተገዛ ፡ ፈጽሞ ፡ ይገረዝ ። ቃል ፡ ኪዳኔም ፡ በሥጋችሁ ፡ ፲፬ የዘላለም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ይሆናል ። የቍልፈቱን ፡ ሥጋ ፡ ያልተገረዘ ፡ ቈላፍ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፥ ያች ፡ ነፍስ ፡ ከወገንዋ ፡ ተለይታ ፡ ትጥፋ ፤ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ አፍርሳለችና ።

፲፭ እግዚአብሔርም ፡ አብርሃምን ፡ አለው ፡— የሚስትህን ፡ የሦራን ፡ ስም ፡ ሦራ ፡ ብለህ ፡ አትጥራ ፥ ፲፮ ስምዋ ፡ ሣራ ፡ ይሆናል ፡ እንጂ ። እባርካታለሁ ፥ ደግሞም ፡ ከእርስዋ ፡ ልጅ ፡ እሰጥሃለሁ ፤ እባርካትማለሁ ፥ የአሕዛብም ፡ እናት ፡ ትሆናለች ፤ የአሕዛብ ፡ ነገሥታት ፡ ከእርስዋ ፡ ይወጣሉ ። ፲፯ አብርሃምም ፡ በግምባሩ ፡ ወደቀ ፥ ሳቀም ፥ በልቡም ፡ አለ ፡— የመቶ ፡ ዓመት ፡ ሰው ፡ በውኑ ፡ ልጅ ፡ ይወለድለታልን ? ዘጠና ፡ ዓመት ፡ የሆናትም ፡ ፲፰ ሣራ ፡ ትወልዳለችን ? አብርሃምም ፡ እግዚአብሔርን ፡— እስማኤል ፡ በፊትህ ፡ ቢኖር ፡ ፲፱ በወደድሁ ፡ ነበር ፡ አለው ። እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡— በእውነት ፡ ሚስትህ ፡ ሣራ ፡ ወንድ ፡ ልጅን ፡ ትወልድልሃለች ፥ ስሙንም ፡ ይስሐቅ ፡ ብለህ ፡ ትጠራዋለህ ፤ ከእርሱ ፡ በኋላ ፡ ለዘሩ ፡ የዘላለም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ እንዲሆን ፡ ቃል ፡ ኪዳ ፳ ኔን ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አቆማለሁ ። ስለ ፡ እስማኤልም ፡ ሰምቼሃለሁ ፤ እነሆ ፡ ባርኬዋለሁ ፥ ፍሬያምም ፡ አደርገዋለሁ ፥ እጅግም ፡ አበዛዋለሁ ፤ አሥራ ፡ ሁለት ፡ አለቆችንም ፡ ይወልዳል ፥ ታላቅ ፡ ሕዝብም ፡ እንዲሆን ፡ አደርገዋለሁ ። ፳፩ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ ግን ፡ በሚመጣው ፡ ዓመት ፡ በዚሁ ፡ ጊዜ ፡ ሣራ ፡ ከምትወልድልህ ፡ ከይስሐቅ ፡ ጋር ፡ አቆማለሁ ።

፳፪ ንግግሩንም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአብርሃም ፡ ተለይቶ ፡ ወጣ ። ፳፫ አብርሃምም ፡ ልጁን ፡ እስማኤልን ፥ በቤቱም ፡ የተወለዱትን ፡ ሁሉ ፥ በብሩም ፡ የገዛቸውን ፡ ሁሉ ፥ ከአብርሃም ፡ ቤት ፡ ሰብ ፡ ወንዶቹን ፡ ሁሉ ፡ ወሰደ ፥ የቍልፈታቸውንም ፡ ሥጋ ፡ እግዚአብ ፳፬ ሔር ፡ እንዳለው ፡ በዚያው ፡ ቀን ፡ ገረዘ ። አብርሃምም ፡ የቍልፈቱን ፡ ሥጋ ፡ በተገረዘ ፡ ጊዜ ፡ ፳፭ የዘጠና ፡ ዘጠኝ ፡ ዓመት ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ልጁ ፡ እስማኤልም ፡ የቍልፈቱን ፡ ሥጋ ፡ በተገረዘ ፡ ጊዜ ፡ የአሥራ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ። ፳፮ በዚያው ፡ ቀን ፡ አብርሃም ፡ ተገረዘ ፥ ልጁ ፡ እስ ፳፯ ማኤልም ። በቤት ፡ የተወለዱትና ፡ በብር ፡ ከእንግዶች ፡ የተገዙት ፥ የቤቱ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተገረዙ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ በቀትርም ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ በድንኳኑ ፡ ደጃፍ ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመምሬ ፡ የአ ፪ ድባር ፡ ዛፍ ፡ ተገለጠለት ። ዓይኑንም ፡ አነሣና ፡ እነሆ ፥ ሦስት ፡ ሰዎች ፡ በፊቱ ፡ ቆመው ፡ አየ ፤ ባያቸውም ፡ ጊዜ ፡ ሊቀበላቸው ፡ ከድንኳኑ ፡ ደጃፍ ፡ ተነሥቶ ፡ ሮጠ ፥ ወደ ፡ ምድርም ፡ ሰገደ ፥ ፫ እንዲህም ፡ አለ ፡— አቤቱ ፥ በፊትህስ ፡ ሞገስ ፡ አግኝቼ ፡ እንደ ፡ ሆን ፡ ባሪያህን ፡ አትለፈኝ ፡ ፬ ብዬ ፡ እለምናለሁ ፤ ጥቂት ፡ ውኃ ፡ ይምጣላችሁ ፥ እግራችሁን ፡ ታጠቡ ፥ ከዚህችም ፡ ዛፍ ፡ ፭ በታች ፡ ዕረፉ ፤ ቍራሽ ፡ እንጀራም ፡ ላምጣላችሁ ፥ ልባችሁንም ፡ ደግፉ ፡ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ትሄዳላችሁ ፤ ስለዚህ ፡ ወደ ፡ ባሪያችሁ ፡ መጥታችኋልና ። እነርሱም ፡— እንዳልህ ፡ አድርግ ፡ ፮ አሉት ። አብርሃምም ፡ ወደ ፡ ድንኳን ፡ ወደ ፡ ሣራ ፡ ዘንድ ፡ ፈጥኖ ፡ ገባና ፡— ሦስት ፡ መስፈሪያ ፡ የተሰለቀ ፡ ዱቄት ፡ ፈጥነሽ ፡ አዘጋጂ ፥ ለውሺውም ፥ እንጎቾም ፡ አድርጊ ፡ አላት ። ፯ አብርሃምም ፡ ወደ ፡ ላሞቹ ፡ ሮጠ ፥ እጅግ ፡ የሰባም ፡ ታናሽ ፡ ጥጃ ፡ ያዘና ፡ ለብላቴናው ፡ ሰጠው ፥ ያዘጋጅም ፡ ዘንድ ፡ ተቻኰለ ። ፰ እርጎና ፡ ወተትም ፡ ያዘጋጀውንም ፡ ጥጃ ፡ አመጣ ፥ በፊታቸውም ፡ አቀረበው ፤ እርሱም ፡ ከዛፉ ፡ በታች ፡ በፊታቸው ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፥ እነርሱም ፡ በሉ ።

፱ እነርሱም ፡— ሚስትህ ፡ ሣራ ፡ ወዴት ፡ ናት ? አሉት ። እርሱም ፡— በድንኳኑ ፡ ውስጥ ፡ ናት ፡ ፲ አላቸው ። እርሱም ፡— የዛሬ ፡ ዓመት ፡ እንደ ፡ ዛሬው ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ በእውነት ፡ እመለሳለሁ ፤ ሚስትህ ፡ ሣራም ፡ ልጅን ፡ ታገኛለች ፡ አለ ። ሣራም ፡ በድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ በስተ ፡ ኋላው ፡ ፲፩ ሳለች ፡ ይህንን ፡ ሰማች ። አብርሃምና ፡ ሣራም ፡ በዕድሜአቸው ፡ ሸምግለው ፡ ፈጽመው ፡ አርጅተው ፡ ነበር ፤ በሴቶች ፡ የሚሆነውም ፡ ልማድ ፡ ፲፪ ከሣራ ፡ ተቋርጦ ፡ ነበር ። ሣራም ፡ በልብዋ ፡ እንዲህ ፡ ስትል ፡ ሳቀች ፡— ካረጀሁ ፡ በኋላ ፡ በውኑ ፡ ፍትወት ፡ ይሆንልኛልን ? ጌታዬም ፡ ፲፫ ፈጽሞ ፡ ሸምግሎአል ። እግዚአብሔርም ፡ አብርሃምን ፡ አለው ፡— ካረጀሁ ፡ በኋላ ፡ በውኑ ፡ እወልዳለሁን ? ስትል ፡ ሣራ ፡ ስምን ፡ ሳቀች ? ፲፬ በውኑ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚሳነው ፡ ነገር ፡ አለን ? የዛሬ ፡ ዓመት ፡ እንደ ፡ ዛሬው ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እመለሳለሁ ፤ ሣራም ፡ ልጅን ፡ ፲፭ ታገኛለች ። ሣራም ፡ ስለ ፡ ፈራች ፡— አልሳቅሁም ፡ ስትል ፡ ካደች ። እርሱም ፡— አይደለም ፥ ሳቅሽ ፡ እንጂ ፡ አላት ።

፲፮ ሰዎቹም ፡ ከዚያ ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ ሰዶም ፡ አቀኑ ፤ አብርሃምም ፡ ሊሸኛቸው ፡ አብሮአቸው ፡ ፲፯ ሄደ ። እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡— እኔ ፡ የማደ ፲፰ ርገውን ፡ ከአብርሃም ፡ እሰውራለሁን ? አብርሃም ፡ በእውነት ፡ ታላቅና ፡ ብርቱ ፡ ሕዝብ ፡ ይሆናልና ፥ የምድር ፡ አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ በእ ፲፱ ርሱ ፡ ይባረካሉና ። ጽድቅንና ፡ ፍርድን ፡ በማድረግ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንገድ ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ልጆቹንና ፡ ከእርሱ ፡ በኋላ ፡ ቤቱን ፡ እንዲያዝዝ ፡ አውቃለሁና ፤ ይህም ፡ እግዚአብሔር ፡ በአብርሃም ፡ ላይ ፡ የተናገረውን ፡ ነገር ፡ ፳ ሁሉ ፡ ያመጣ ፡ ዘንድ ፡ ነው ። እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡— የሰዶምና ፡ የገሞራ ፡ ጩኸት ፡ እጅግ ፡ በዝቶአልና ፥ ኃጢአታቸውም ፡ እጅግ ፡ ከብዳ ፳፩ ለችና ፥ እንግዲህስ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንደ ፡ መጣች ፡ እንደ ፡ ጩኸትዋ ፡ አድርገው ፡ እንደ ፡ ሆን ፡

ወርጄ ፡ እያለሁ ፤ እንዲሁም ፡ ባይሆን ፡ አው
ቃለሁ ።
፳፪ ሰዎቹም ፡ ከዚያ ፡ ፊታቸውን ፡ አቀኑ ÷ ወደ ፡
ሰዶምም ፡ ሄዱ ፤ አብርሃም ፡ ግን ፡ በእግዚአብ
፳፫ ሔር ፡ ፊት ፡ ገና ፡ ቆሞ ፡ ነበር ። አብርሃምም ፡
ቀረበ ፡ አለም ፡— በውኑ ፡ ጻድቁን ፡ ከኃጢአ
፳፬ ተኛ ፡ ጋር ፡ ታጠፋለህን ? አምሳ ፡ ጻድቃን ፡ በከ
ተማይቱ ፡ ውስጥ ፡ ቢገኙ ፡ በውኑ ፡ ሁሉን ፡ ታጠ
ፋለህን ? ከተማይቱንስ ፡ በእርስዋ ፡ ስለሚገኙ ፡
፳፭ አምሳ ፡ ጻድቃን ፡ አትምርምን ? ይህ ፡ ከአንተ ፡
ይራቅ ፤ ጻድቁን ፡ ከኃጢአተኛ ፡ ጋር ፡ ትገድል ፡
ዘንድ ÷ ጻድቁም ፡ እንደ ፡ ኃጢአተኛ ፡ ይሆን ፡
ዘንድ ÷ እንደዚህ ፡ ያለው ፡ አድራጎት ፡ ከአንተ ፡
ይራቅ ። የምድር ፡ ሁሉ ፡ ፈራጅ ፡ በቅን ፡ ፍርድ ፡
፳፮ አይፈርድምን ? እግዚአብሔርም ፡— በሰዶም ፡
በከተማይቱ ፡ ውስጥ ፡ አምሳ ፡ ጻድቃን ፡ ባገኝ ፡
ስፍራውን ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ እምራለሁ ፡ አለ ።
፳፯ አብርሃምም ፡ መለሰ ፡ አለም ፡— እኔ ፡ አፈርና ፡
አመድ ፡ ስሆን ፡ ከጌታዬ ፡ ጋር ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡
፳፰ እነሆ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ጀመርሁ ፤ ከአምሳው ፡
ጻድቃን ፡ አምስት ፡ ቢጐድሉ ፡ ከተማይቱን ፡
ሁሉ ፡ በአምስቱ ፡ ምክንያት ፡ ታጠፋለህን ?
ከዚያ ፡ አርባ ፡ አምስት ፡ ባገኝ ፡ አላጠፋትም ፡ አለ ።
፳፱ ደግሞም ፡ ተናገረው ÷ እንዲህም ፡ አለ ፡—ምና
ልባት ፡ ከዚያ ፡ አርባ ፡ ቢገኙሳ ? እርሱም ፡—
፴ ለአርባው ፡ ስል ፡ አላደርገውም ፡ አለ ። እርሱም ፡—
ጌታዬ ፡ አይቆጣ ፡ እኔም ፡ እናገራለሁ ፡ ምናል
ባት ፡ ከዚያ ፡ ሠላሳ ፡ ቢገኙሳ ? አለ ። እርሱም ፡—
፴፩ ከዚያ ፡ ሠላሳ ፡ ባገኝ ፡ አላጠፋም ፡ አለ ። ደግ
ሞም ፡— እነሆ ÷ ከጌታዬ ፡ ጋር ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡
አንድ ፡ ጊዜ ፡ ጀመርሁ ፤ ምናልባት ፡ ከዚያ ፡
ሀያ ፡ ቢገኙሳ ? አለ ። እርሱም ፡— ከዚያ ፡ ሀያ ፡
ቢገኙ ፡ ስለ ፡ ሀያው ፡ አላደርገውም ፡ አለ ።
፴፪ እርሱም ፡— እኔ ፡ ደግሞ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡
ብናገር ፡ ጌታዬ ፡ አይቆጣ ፤ ምናልባት ፡ ከዚያ ፡
አሥር ፡ ቢገኙሳ ? አለ ። እርሱም ፡— ስለ ፡
፴፫ አሥሩ ፡ አላጠፋትም ፡ አለ ። እግዚአብሔርም ፡
ከአብርሃም ፡ ጋር ፡ ንግግሩን ፡ በጨረሰ ፡ ጊዜ ፡
ሄደ ፤ አብርሃምም ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ተመለሰ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ ሁለቱም ፡ መላእክት ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡
ሰዶም ፡ ገቡ ፤ ሎጥም ፡ በሰዶም ፡ በር ፡ ተቀምጦ ፡
ነበር ። ሎጥም ፡ ባያቸው ፡ ጊዜ ፡ ሊቀበላቸው ፡
ተነሣ ፤ ፊቱንም ፡ ደፍቶ ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ሰገደ ÷
፪ አላቸውም ፡— ጌቶቼ ፡ ሆይ ÷ ወደ ፡ ባሪያችሁ ፡
ቤት ፡ አቅኑ ÷ ከዚያም ፡ እደሩ ÷ እግራችሁ
ንም ፡ ታጠቡ ፤ ነገ ፡ ማልዳችሁም ፡ መንገዳች
ሁን ፡ ትሄዳላችሁ ። እነርሱም ፡— በአደባባዩ ፡
፫ እናድራለን ፡ እንጂ ÷ አይሆንም ፡ አሉት ። እጅ
ግም ፡ ዘበዘባቸው ፤ ወደ ፡ እርሱም ፡ አቀኑ ÷
ወደ ፡ ቤቱም ፡ ገቡ ፤ ማዕድ ፡ አቀረበላቸው ÷
፬ ቂጣንም ፡ ጋገረ ፡ እነርሱም ፡ በሉ ። ገናም ፡ ሳይ
ተኙ ፡ የዚያች ፡ ከተማ ፡ የሰዶም ፡ ሰዎች ÷ ከብ
ላቴናው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሽማግሌው ፡ ድረስ ÷
በየስፍራው ፡ ያለው ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ÷ ቤቱን ፡
፭ ከበቡት ። ሎጥንም ፡ ጠርተው ፡ እንዲህ ፡
አሉት ፡— በዚህ ፡ ሌሊት ፡ ወደ ፡ቤትህ ፡ የገ
ቡት ፡ ሰዎች ፡ ወዴት ፡ ናቸው ? እናውቃቸው ፡
፮ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ አውጣቸው ። ሎጥም ፡ ወደ ፡
እነርሱ ፡ ወደ ፡ ደጅ ፡ ወጣ ፡ መዝጊያውንም ፡
፯ በኋላው ፡ ዘጋው ፤ እንዲህም ፡ አለ ፡— ወንድ
ሞቼ ፡ ሆይ ÷ ይህን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አታድርጉ ፤
፰ እነሆ ÷ ወንድን ፡ ያላወቁ ፡ ሁለት ፡ ሴቶች ፡
ልጆች ፡ አሉኝ ፤ እነርሱን ፡ ላውጣላችሁ ÷ እንደ ፡
ወደዳችሁም ፡ አድርጓቸው ፤ በእነዚህ ፡ ሰዎች ፡
ብቻ ፡ ምንም ፡ አታድርጉ ÷ እነርሱ ፡ በጣራዬ ፡
፱ ጥላ ፡ሥር ፡ ገብተዋልና ። እነርሱም ፡— ወዲያ ፡
ሂድ ፡ አሉት ። ደግሞም ፡ እንዲህ ፡ አሉ ፡—ይህ ፡
ሰው ፡ በእንግድነት ፡ ለመኖር ፡ መጣ ÷ ፍርዱ
ንም ፡ ይፈርድ ፡ ዘንድ ፡ ይፈልጋል ፤ አሁን ፡ በአ
ንተ ፡ ከእነርሱ ፡ ይልቅ ፡ ክፉ ፡ እናደርግብሃለን ።
ሎጥንም ፡ እጅግ ፡ ተጋፉት ÷ የደጁንም ፡ መዝ
፲ ጊያ ፡ ለመስበር ፡ ቀረቡ ። ሁለቱም ፡ ሰዎች ፡
እጃቸውን ፡ዘርግተው ፡ ሎጥን ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ አገቡት ፡ መዝጊያውንም ፡
፲፩ ዘጉት ። በቤቱ ፡ ደጃፍ ፡ የነበሩትንም ፡ ሰዎች ፡
ከታናሻቸው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታላቃቸው ፡
ድረስ ፡ አሳወሩአቸው ፤ ደጃፉንም ፡ ለማግኘት ፡
ሲፈልጉ ፡ ደከሙ ።
፲፪ ሁለቱም ፡ ሰዎች ፡ ሎጥን ፡ አሉት ፡— ከዚህ ፡
ሌላ ፡ ማን ፡ አለህ ? አማችም ፡ ቢሆን ፡ ወንድ ፡
ልጅም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ብትሆን ፡
በከተማይቱ ፡ ያለህን ፡ ሁሉ ፡ ከዚህ ፡ ስፍራ ፡
፲፫ አስወጣቸው ፤ እኛ ፡ ይህን ፡ ስፍራ ፡ እናጠፋ
ለንና ÷ ጩኸታቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ትልቅ ፡ ሆኖአልና ፤ እናጠፋውም ፡ ዘንድ ፡ እግ
፲፬ ዚአብሔር ፡ ሰዶናል ። ሎጥም ፡ ወጣ ÷ ልጆ
ቹን ፡ ለሚያገቡት ፡ ለአማቾቹም ፡ ነገራቸው ÷
አላቸውም ፡— ተነሡ ፤ ከዚህ ፡ ስፍራ ፡ ውጡ ፤
እግዚአብሔር ፡ ይህችን ፡ ከተማ ፡ ያጠፋልና ።
ለአማቾቹ ፡ ግን ፡ የሚያፌዝባቸው ፡ መሰላቸው ።
፲፭ ጎህም ፡ በቀደደ ፡ ጊዜ ፡ መላእክት ፡ ሎጥን ፡—
ተነሣ ÷ሚስትህንና ፡ ከዚህ ፡ ያሉትን ፡ ሁለ
ቱን ፡ ሴቶች ፡ ልጆችህን ፡ ውሰድ ፤ በከተማ
ይቱ ፡ ኃጢአት ፡ እንዳትጠፋ ፡ እያሉ ፡ ያስቸኩ
፲፮ ሉት ፡ ነበር ። እርሱም ፡ በዘገየ ፡ ጊዜ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ስላዘነለት ፡ እነዚያ ፡ ሰዎች ፡ የእር
ሱን ፡ እጅ ፡ የሚስቱንም ፡ እጅ ፡ የሁለቱን ፡ የሴ
ቶች ፡ ልጆቹንም ፡ እጅ ፡ ያዘው ፡ አወጡትና ፡
፲፯ በከተማይቱ ፡ ውጭ ፡ አስቀመጡት ። ወደ ፡
ሜዳም ፡ ከወጡአቸው ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡—
ራስህን ፡ አድን ፤ ወደ ፡ ኋላህ ፡ አትይ ÷ በዚ
ህም ፡ ዙሪያ ፡ ሁሉ ፡ አትቁም ፤ እንዳትጠፋም ፡
፲፰ ወደ ፡ ተራራው ፡ ሸሽተህ ፡ አምልጥ ። ሎጥም ፤
አላቸው ፡ — ጌቶቼ ፡ ሆይ ÷ እንዲህስ ፡ አይሁን ፤
፲፱ እነሆ ፡ ባሪያህ ፡ በፊትህ ፡ ሞገስን ፡ አግኝቶአል ÷
ነፍሴን ፡ ለማዳን ፡ ያደረግህልኝን ፡ ምሕረትህ

ንም ፡ አብዝተሃል ፤ ክፉ ፡ እንዳያገኘኝና ፡ እንዳልሞት ፡ ወደ ፡ ተራራ ፡ ሸሽቼ ፡ አመልጥ ፡ ዘንድ ፡ አልችልም ፤ ፳ እነሆ ፡ ይህች ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ሸሽቶ ፡ ለማምለጥ ፡ ቅርብ ፡ ናት ፥ እርስዋም ፡ ትንሽ ፡ ናት ፤ ነፍሴን ፡ ለማዳን ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ሸሽቼ ፡ ላምልጥ ፤ እርስዋ ፡ ትንሽ ፡ ከተማ ፡ አይደለችምን ? ፳፩ እርሱም ፡ አለው ፡— የተናገርሃትን ፡ ከተማ ፡ እንዳላጠፋት ፡ እነሆ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ የለመንኸኝን ፡ ተቀብዬሃለሁ ፤ ፳፪ በቶሎ ፡ ወደዚያ ፡ ሸሽተህ ፡ አምልጥ ፤ ወደዚያ ፡ እስክትደርስ ፡ ድረስ ፡ ምንም ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ አልችልምና ። ስለዚህም ፡ የዚያች ፡ ከተማ ፡ ስም ፡ ዞዓር ፡ ተባለ ።

፳፫ ሎጥ ፡ ወደ ፡ ዞዓር ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ፀሐይ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ወጣች ። ፳፬ እግዚአብሔርም ፡ በሰዶምና ፡ በገሞራ ፡ ላይ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ከሰማይ ፡ እሳትና ፡ ዲን ፡ አዘነበ ፤ ፳፭ እነዚያንም ፡ ከተሞች ፥ በዙሪያቸው ፡ ያለውንም ፡ ሁሉ ፥ በከተሞቹም ፡ የሚኖሩትን ፡ ሁሉ ፥ የምድሩንም ፡ ቡቃያ ፡ ሁሉ ፡ ገለበጠ ። ፳፮ የሎጥም ፡ ሚስት ፡ ወደ ፡ ኋላዋ ፡ ተመለከተች ፥ የጨው ፡ ሐውልትም ፡ ሆነች ። ፳፯ አብርሃምም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቆሞ ፡ ወደ ፡ ነበረበት ፡ ስፍራ ፡ ለመሄድ ፡ ማልዶ ፡ ተነሣ ፤ ፳፰ ወደ ፡ ሰዶምና ፡ ወደ ፡ ገሞራ ፡ በዚያች ፡ አገር ፡ ወዳለውም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ተመለከተ ፤ እነሆም ፡ የአገሪቱ ፡ ጢስ ፡ እንደ ፡ እቶን ፡ ጢስ ፡ ሲነሣ ፡ አየ ።

፳፱ እግዚአብሔርም ፡ እነዚያን ፡ የአገር ፡ ከተሞች ፡ ባጠፋ ፡ ጊዜ ፡ አብርሃምን ፡ አሰበው ፤ ሎጥ ፡ ተቀምጦበት ፡ የነበረውንም ፡ ከተማ ፡ ባጠፋ ፡ ጊዜ ፡ ከዚያ ፡ ጥፋት ፡ መካከል ፡ ሎጥን ፡ አወጣው ።

፴ ሎጥም ፡ ከዞዓር ፡ ወጣ ፤ በዞዓር ፡ ይቀመጥ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ፈራም ፡ ከሁለቱ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቹ ፡ ጋር ፡ በተራራ ፡ ተቀመጠ ፤ በዋሻም ፡ ከሁለቱ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቹ ፡ ጋር ፡ ተቀመጠ ። ፴፩ ታላቂቱም ፡ ታናሺቱን ፡ አለቻት ፡— አባታችን ፡ ሸመገለ ፥ በምድርም ፡ ሁሉ ፡ እንዳለው ፡ ልማድ ፡ ሊገናኘን ፡ የሚችል ፡ ሰው ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ የለም ፤ ፴፪ ነዪ ፡ አባታችንንም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ እናጠጣውና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ እንተኛ ፥ ከአባታችንም ፡ ዘር ፡ እናስቀር ። ፴፫ በዚያችም ፡ ሌሊት ፡ አባታቸውን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ አጠጡት ፤ ታላቂቱም ፡ ገባች ፥ ከአባትዋም ፡ ጋር ፡ ተኛች ፤ እርሱም ፡ ስትተኛና ፡ ስትነሣ ፡ አላወቀም ። ፴፬ በነጋውም ፡ ታላቂቱ ፡ ታናሺቱን ፡ አለቻት ፡— እነሆ ፡ ትናንት ፡ ከአባቴ ፡ ጋር ፡ ተኛሁ ፤ ዛሬ ፡ ሌሊት ፡ ደግሞ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ እናጠጣው ፡ አንቺም ፡ ግቢና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተኚ ፥ ከአባታችንም ፡ ዘር ፡ እናስቀር ። ፴፭ አባታቸውንም ፡ በዚያች ፡ ሌሊት ፡ ደግሞ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ አጠጡት ፤ ታናሺቱም ፡ ገብታ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተኛች ፤ እርሱም ፡ ስትተኛና ፡ ስትነሣ ፡ አላወቀም ። ፴፮ የሎጥም ፡ ሁለቱ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ከአባታቸው ፡ ፀነሱ ። ፴፯ ታላቂቱም ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፡ ስሙንም ፡ ሞዓብ ፡ ብላ ፡ ጠራችው ፤ እርሱም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ የሞዓብውያን ፡ አባት ፡ ነው ። ፴፰ ታናሺቱም ፡ ደግሞ ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፡ ስሙንም ፡— የወገኔ ፡ ልጅ ፡ ስትል ፡ አሞን ፡ ብላ ፡ ጠራችው ፤ እርሱም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ የአሞናውያን ፡ አባት ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ አብርሃምም ፡ ከዚያ ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ አዜብ ፡ ምድር ፡ ሄደ ፥ በቃዴስና ፡ በሱር ፡ መካከልም ፡ ተቀመጠ ፤ በጌራራም ፡ በእንግድነት ፡ ተቀመጠ ። ፪ አብርሃምም ፡ ሚስቱን ፡ ሣራን ፡— እኅቴ ፡ ናት ፡ አለ ፤ የጌራራ ፡ ንጉሥ ፡ አቢሜሌክም ፡ ላከና ፡ ሣራን ፡ ወሰዳት ። ፫ እግዚአብሔርም ፡ ሌሊት ፡ በሕልም ፡ ወደ ፡ አቢሜሌክ ፡ መጣ ፥ እንዲህም ፡ አለው ፡— እነሆ ፥ አንተ ፡ ስለ ፡ ወሰድሃት ፡ ሴት ፡ ምውት ፡ ነህ ፤ እርስዋ ፡ ባለ ፡ ባል ፡ ናትና ። ፬ አቢሜሌክ ፡ ግን ፡ አልቀረባትም ፡ ነበር ፤ እንዲህም ፡ አለ ፡— አቤቱ ፥ ጻድቁን ፡ ሕዝብ ፡ ደግሞ ፡ ታጠፋለህን ? ፭ እኅቴ ፡ ናት ፡ ያለኝ ፡ እርሱ ፡ አይደለምን ? እርስዋም ፡ ደግሞ ፡ ራስዋ ፡— ወንድሜ ፡ ነው ፡ አለች ፤ በልቤ ፡ ቅንነትና ፡ በእጄ ፡ ንጹሕነት ፡ ይህንን ፡ አደረግሁ ። ፮ እግዚአብሔርም ፡ በሕልም ፡ አለው ፡— ይህን ፡ በልብህ ፡ ቅንነት ፡ እንዳደረግህ ፡ እኔ ፡ አወቅሁ ፥ እኔም ፡ ደግሞ ፡ በፊቴ ፡ ኃጢአትን ፡ እንዳትሠራ ፡ ከለከልሁህ ፤ ስለዚህም ፡ ትነካት ፡ ዘንድ ፡ አልተውሁም ። ፯ አሁንም ፡ የሰውዮውን ፡ ሚስት ፡ መልስ ፤ ነቢይ ፡ ነውና ፥ ስለ ፡ አንተም ፡ ይጸልያል ፥ ትድናለህም ። ባትመልሳት ፡ ግን ፡ አንተ ፡ እንድትሞት ፡ ለአንተ ፡ የሆነውም ፡ ሁሉ ፡ እንዲሞት ፡ በእርግጥ ፡ እወቅ ።

፰ አቢሜሌክም ፡ በነገታው ፡ ማለደ ፥ ባሪያዎቹንም ፡ ሁሉ ፡ ጠራ ፥ ይህንንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በጆሮአቸው ፡ ተናገረ ፤ ሰዎቹም ፡ እጅግ ፡ ፈሩ ። ፱ አቢሜሌክም ፡ አብርሃምን ፡ ጠርቶ ፡ አለው ፡— ይህ ፡ ያደረግህብን ፡ ምንድር ፡ ነው ? ምን ፡ ክፉ ፡ ሠራሁብህ ? በእኔና ፡ በመንግሥቴ ፡ ላይ ፡ ትልቅ ፡ ኃጢአት ፡ አውርደሃልና ፤ የማይገባ ፡ ሥራ ፡ በእኔ ፡ ሠራህብኝ ። ፲ አቢሜሌክም ፡ አብርሃምን ፡ አለው ፡— ይህን ፡ ማድረግህ ፡ ምን ፡ አይተህ ፡ ነው ? ፲፩ አብርሃምም ፡ አለ ፡— በዚህ ፡ ስፍራ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ በእውነት ፡ እንደሌለ ፥ ለሚስቴም ፡ ሲሉ ፡ እንደሚገድሉኝ ፡ ስላሰብሁ ፡ ነው ። ፲፪ እርስዋም ፡ ደግሞ ፡ በእውነት ፡ እኅቴ ፡ ናት ፤ የእናቴ ፡ ልጅ ፡ አይደለችም ፡ እንጂ ፡ የአባቴ ፡ ልጅ ፡ ናት ፤ ለእኔም ፡ ሚስት ፡ ሆነች ። ፲፫ እግዚአብሔርም ፡ ከአባቴ ፡ ቤት ፡ ባወጣኝ ፡ ጊዜ ፡ አልኋት ፡— በገባንበት ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ለእኔ ፡ የምታደርጊው ፡ ወሮታ ፡ ይህ ፡ ነው ፡— ወንድሜ ፡ ነው ፡ በለሽ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ ተናገሪ ። ፲፬ አቢሜሌክም ፡ በጎችንና ፡ ላሞችን ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ባሪያዎችን ፡ አመጣ ፥ ለአብርሃምም ፡ ሰጠው ፥ ሚስቱን ፡ ሣራንም ፡ መለሰለት ። ፲፭ አቢ

ሜሌክም ፡— እነሆ ፥ ምድሬ ፡ በፊትህ ፡ ናት ፤
፲፮ በወደድኸው ፡ ተቀመጥ ፡ አለ ። ሣራንም ፡
አላት ፡— እነሆ ፥ ለወንድምሽ ፡ ሺህ ፡ሚዛን ፡
ብር ፡ ሰጠሁት ፤ ያም ፡ እነሆ ፡ ከአንቺ ፡ ጋር ፡
ባሉት ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ የዓይኖች ፡ መሸፈኛ ፡ ይሁ
ንሽ ፤ ጽድቅሽ ፡ ለሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ተገለጠአልና ።
፲፯ አብርሃምም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸለየ ፤ እግ
ዚአብሔርም ፡ አቢሜሌክን ፡ ሚስቱንም ፡ ባሪያ
፲፰ ዎቹንም ፡ ፈወሳቸው ፥ እነርሱም ፡ ወለዱ ፤ እግ
ዚአብሔር ፡ በአብርሃም ፡ ሚስት ፡ በሣራ ፡ ምክ
ንያት ፡ በአቢሜሌክ ፡ ቤት ፡ ማኅፀኖችን ፡ ሁሉ ፡
በፍጹም ፡ ዘግቶ ፡ ነበርና ።

ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ ሣራን ፡
አሰበ ፤ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡
፪ ለሣራ ፡ አደረገላት ። ሣራም ፡ ፀነሰች ፥ እግዚ
አብሔርም ፡ በተናገረው ፡ ወራት ፡ ለአብርሃም ፡
በእርጅናው ፡ ወንድ ፡ ልጅን ፡ ወለደችለት ።
፫ አብርሃምም ፡ የተወለደለትን ፡ ሣራ ፡ የወለደች
ለትን ፡ የልጁን ፡ ስም ፡ ይስሐቅ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።
፬ አብርሃምም ፡ ልጁን ፡ ይስሐቅን ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ በስምንተኛ ፡ ቀን ፡ ገረዘው ።
፭ አብርሃምም ፡ ልጁ ፡ ይስሐቅ ፡ በተወለደለት ፡
፮ ጊዜ ፡ የመቶ ፡ ዓመት ፡ ዕድሜ ፡ ነበረ ። ሣራም ፡—
እግዚአብሔር ፡ ሳቅ ፡ አድርጎልኛል ፤ ይህንንም ፡
የሚሰማ ፡ ሁሉ ፡ በእኔ ፡ ምክንያት ፡ ይስቃል ፡
፯ አለች ። ደግሞም ፡— ሣራ ፡ ልጆችን ፡ እንድታ
ጠባ ፡ ለአብርሃም ፡ ማን ፡ በነገረው ? በእርጅ
ናው ፡ ልጅን ፡ ወልጄለታለሁና ፡ አለች ።
፰ ሕፃኑም ፡ አደገ ፥ ጡትንም ፡ ከመጥባት ፡ ተቋ
ረጠ ፤ አብርሃምም ፡ ይስሐቅን ፡ ጡት ፡ ባስጣለ
፱ በት ፡ ቀን ፡ ትልቅ ፡ ግብዣን ፡ አደረገ ። ሣራም ፡
ግብፃዊቱ ፡ አጋር ፡ ለአብርሃም ፡ የወለደችለትን ፡
፲ ልጅ ፡ ሲስቅ ፡ አየችው ። አብርሃምንም ፡—
ይህችን ፡ ባሪያ ፡ ከነልጅዋ ፡ አሳድድ ፤ የዚህች ፡
ባሪያ ፡ ልጅ ፡ ከልጄ ፡ ከይስሐቅ ፡ ጋር ፡ አይወ
፲፩ ርስምና ፡ አለችው ። ይህም ፡ ነገር ፡ በአብርሃም ፡
ዘንድ ፡ ስለ ፡ ልጁ ፡ እጅግ ፡ ችግር ፡ ሆነበት ።
፲፪ እግዚአብሔርም ፡ አብርሃምን ፡ አለው ፡— ስለ ፡
ባሪያህና ፡ ስለ ፡ ብላቴናው ፡ አትዘን ፤ ሣራም ፡
የምትነግርህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ስማ ፤ በይስሐቅ ፡
፲፫ ዘር ፡ ይጠራልሃልና ። የባሪያይቱን ፡ ልጅ ፡
ደግሞ ፡ ሕዝብ ፡ አደርገዋለሁ ፥ ዘርህ ፡ ነውና ።
፲፬ አብርሃምም ፡ ማልዶ ፡ ተነሣ ፥ እንጀራንም ፡
ወሰደ ፥ የውኃ ፡ አቁማዳንም ፡ ለአጋር ፡ በትከ
ሻዋ ፡ አሸከማት ፥ ብላቴናውንም ፡ ሰጥቶ ፡ አሰ
ወጣት ፤ እርስዋም ፡ ሄደች ፡ በቤርሳቤህም ፡
፲፭ ምድረ ፡ በዳ ፡ ተቅበዘበዘች ። ውኃውም ፡ ከአ
ቁማዳው ፡ አለቀ ፤ ብላቴናውንም ፡ ከአንድ ፡
፲፮ ቍጥቋጦ ፡ በታች ፡ ጣለችው ፤ እርስዋም ፡
ሄደች ፡— ብላቴናው ፡ ሲሞት ፡ አልየው ፡ ብላ ፡
ቀስት ፡ ተወርውሮ ፡ የሚደርስበትን ፡ ያህል ፡
ርቃ ፡ በአንጻሩ ፡ ተቀመጠች ። ፊት ፡ ለፊትም ፡
ተቀመጠች ፥ ቃልዋንም ፡ አሰምታ ፡ አለቀሰች ።
፲፯ እግዚአብሔርም ፡ የብላቴናውን ፡ድምፅ ፡ ሰማ ፤
የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ከሰማይ ፡ አጋ
ርን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ጠራት ፡—አጋር ፡ ሆይ ፥
ምን ፡ ሆንሽ ? እግዚአብሔር ፡ የብላቴናውን ፡
ድምፅ ፡ ባለበት ፡ ስፍራ ፡ ሰምቶአልና ፡ አት
፲፰ ፍሪ ። ተነሺ ፥ ብላቴናውንም ፡ አንሺ ፥ እጅሽ
ንም ፡ በእርሱ ፡ አጽኚው ፤ ትልቅ ፡ ሕዝብ ፡
፲፱ አደርገዋለሁና ። እግዚአብሔርም ፡ ዓይንዋን ፡
ከፈተላት ፥ የውኃ ፡ ጕድጓድንም ፡ አየች ፤
ሄዳም ፡ አቁማዳውን ፡ በውኃ ፡ሞላች ፥ ብላቴ
፳ ናውንም ፡ አጠጣች ። እግዚአብሔርም ፡ ከብላ
ቴናው ፡ ጋር ፡ ነበረ ፤ አደገም ፥ በምድረ ፡
፳፩ በዳም ፡ ተቀመጠ ፥ ቀስተኛም ፡ ሆነ ። በፋራን ፡
ምድረ ፡ በዳም ፡ ተቀመጠ ፤ እናቱም ፡ ከምድረ ፡
ግብፅ ፡ ሚስት ፡ ወሰደችለት ።
፳፪ በዚያም ፡ ዘመን ፡ አቢሜሌክ ፡ ከሙሽራው ፡
ወዳጅ ፡ ከአኮዘትና ፡ ከሠራዊቱ ፡ አለቃ ፡ ከፊ
ኮል ፡ ጋር ፡ አብርሃምን ፡ አለው ፡— በምታደር
ገው ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡
፳፫ ነው ፤ አሁንም ፡ በእኔም ፡ በልጄም ፡ በልጅ ፡
ልጄም ፡ ክፉ ፡ እንዳታደርግብኝ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ማልልኝ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለአንተ ፡ ቸርነትን ፡
እንዳደረግሁ ፡ አንተም ፡ ለእኔ ፡ ለተቀመጥህባ
፳፬ ትም ፡ ምድር ፡ ቸርነትን ፡ታደርጋለህ ። አብርሃ
፳፭ ምም ፡— እኔ ፡ እምላለሁ ፡ አለ ። አቢሜሌክንም ፡
ባሪያዎቹ ፡ በነጠቁት ፡ በውኃ ፡ ጕድጓድ ፡ ምክን
፳፮ ያት ፡ አብርሃም ፡ ወቀሰው ። አቢሜሌክም ፡
አለ ፡—ይህን ፡ ነገር ፡ ያደረገውን ፡ አላወቅሁም ፤ አን
ተም ፡ ደግሞ ፡ ምንም ፡ አልነገርኸኝም ፥ እኔም ፡
፳፯ ከዛሬ ፡ በቀር ፡ አልሰማሁም ። አብርሃምም ፡
በጎችንና ፡ ላሞችን ፡ አምጥቶ ፡ ለአቢሜሌክ ፡
ሰጠው ፤ ሁለቱም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረጉ ።
፳፰ አብርሃምም ፡ ሰባት ፡ ቄቦች ፡ በጎችን ፡ ለብቻ
፳፱ ቸው ፡ አቆመ ። አቢሜሌክም ፡ አብርሃምን ፡—
ለብቻቸው ፡ ያቆምሃቸው ፡ እነዚህ ፡ ሰባት ፡
፴ ቄቦች ፡ በጎች ፡ ምንድር ፡ ናቸው ? አለው ። እር
ሱም ፡— እኔ ፡ ይህችን ፡ የውኃ ፡ ጕድጓድ ፡ እንደ ፡
ቆፈርሁ ፡ ምስክር ፡ ይሆንልኝ ፡ ዘንድ ፡ እነዚ
ህን ፡ ሰባት ፡ ቄቦች ፡ በጎች ፡ ከእጄ ፡ ትወስዳለህ ፡
፴፩ አለው ። ስለዚህ ፡ የዚያን ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ ቤር
ሳቤህ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ፤ ከዚያ ፡ ሁለቱ ፡ ተማ
፴፪ ምለዋልና ። በቤርሳቤህም ፡ ቃል ፡ ኪዳንን ፡
አደረጉ ። አቢሜሌክና ፡ የሙሽራው ፡ ወዳጅ ፡
አኮዘት ፡ የሠራዊቱ ፡ አለቃ ፡ ፊኮልም ፡ ተነሥተው ፡
፴፫ ወደ ፡ ፍልስጥኤም ፡ ምድር ፡ ተመለሱ ። አብርሃ
ምም ፡ በቤርሳቤህ ፡ የተምር ፡ ዛፍን ፡ ተከለ ፤ በዚ
ያም ፡ የዘላለሙን ፡ አምላክ ፡ የእግዚአብሔርን ፡
፴፬ ስም ፡ ጠራ ። አብርሃምም ፡ በፍልስጥኤም ፡
ምድር ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ እንግዳ ፡ ሆኖ ፡ ተቀመጠ ።

ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ ከእነዚህም ፡ ነገሮች ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡
አብርሃምን ፡ ፈተነው ፥ እንዲህም ፡ አለው ፡—

አብርሃም ፡ ሆይ ። አብርሃምም ፡— እነሆ ÷ አለው ፡ አለ ። ፪ የምትወደውን ፡ አንድ ፡ ልጅህን ፡ ይስሐቅን ፡ ይዘህ ፡ ወደ ፡ ሞሪያም ፡ ምድር ፡ ሂድ ፤ እኔም ፡ በምነግርህ ፡ በአንድ ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ በዚያ ፡ መሥዋዕት ፡ አድርገህ ፡ ሠዋው ፡ አለ ። ፫ አብርሃምም ፡ በማለዳ ፡ ተነሥቶ ፡ አህያውን ፡ ጫነ ÷ ሁለቱንም ፡ ሎሌዎቹንና ፡ ልጁን ፡ ይስሐቅን ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ወሰደ ÷ እንጨትንም ፡ ለመሥዋዕት ፡ ሰነጠቀ ፤ ተነሥቶም ፡ እግዚአብሔር ፡ ወዳለው ፡ ቦታ ፡ ሄደ ። ፬ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ አብርሃም ፡ ዓይኑን ፡ አንሥና ፡ ፭ በታውን ፡ ከሩቅ ፡ አየ ። አብርሃምም ፡ ሎሌዎቹን ፡ አላቸው ፡— አህያውን ፡ ይዛችሁ ፡ ከዚህ ፡ ቆዩ ፤ እኔና ፡ ልጄ ፡ ወደዚያ ፡ ሄደን ፡ እንሰግዳለን ÷ ፮ ወደ ፡ እናንተም ፡ እንመለሳለን ። አብርሃምም ፡ የመሥዋዕቱን ፡ እንጨት ፡ አንሥቶ ፡ ለልጁ ፡ ለይስሐቅ ፡ አሸከመው ፤ እርሱም ፡ እሳቱንና ፡ ቢላዋውን ፡ በእጁ ፡ ያዘ ÷ ሁለቱም ፡ ፯ አብረው ፡ ሄዱ ። ይስሐቅም ፡ አባቱን ፡ አብርሃምን ፡ ተናገረው ፡— አባቴ ፡ ሆይ ፡ አለ ። እርሱም ፡— እነሆኝ ÷ ልጄ ፡ አለው ። እሳቱና ፡ እንጨቱ ፡ ይኸው ፡ አለ ፤ የመሥዋዕቱ ፡ በግ ፡ ግን ፡ ፰ ወዴት ፡ ነው ? አለ ። አብርሃምም ፡— ልጄ ፡ ሆይ ÷ የመሥዋዕቱን ፡ በግ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያዘጋጃል ፡ አለው ፤ ሁለቱም ፡ አብረው ፡ ሄዱ ።

፱ እግዚአብሔር ፡ ወዳለውም ፡ ቦታ ፡ ደረሱ ፤ አብርሃምም ፡ በዚያ ፡ መሠውያውን ፡ ሠራ ÷ እንጨትንም ፡ ረበረበ ፤ ልጁን ፡ ይስሐቅንም ፡ አስሮ ፡ በመሠውያው ፡ በእንጨቱ ፡ ላይ ፡ አጋደመው ። ፲ አብርሃምም ፡ እጁን ፡ ዘረጋ ÷ ልጁንም ፡ ያርድ ፡ ፲፩ ዘንድ ፡ ቢላዋ ፡ አነሣ ። የእግዚአብሔር ፡ መልአክም ፡ ከሰማይ ፡ ጠራና ፡— አብርሃም ፡ አብር ፲፪ ሃም ፡ አለው ፤ እርሱም ፡— እነሆኝ ፡ አለ ። እርሱም ፡— በብላቴናው ፡ ላይ ፡ እጅህን ፡ አትዘርጋ ÷ አንዳችም ፡ አታድርግበት ፤ አንድ ፡ ልጅህን ፡ ለእኔ ፡ አልከለከልህምና ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምትፈራ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ አሁን ፡ አውቄአ ፲፫ ለሁ ፡ አለ ። አብርሃምም ፡ ዓይኑን ፡ አነሣ ÷ በኋላውም ፡ እነሆ ፡ አንድ ፡ በግ ፡ በዱር ፡ ውስጥ ፡ ቀንዶቹ ፡ በዕፀ ፡ ሳቤቅ ፡ ተይዞ ፡ አየ ፤ አብርሃምም ፡ ሄደ ፡ በጉንም ፡ ወሰደው ÷ በልጁም ፡ ፲፬ ፋንታ ፡ መሥዋዕት ፡ አድርጎ ፡ ሠዋው ። አብርሃምም ፡ ያንን ፡ ቦታ ፡ ያህዌ ፡ ይርኤ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ፤ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ በእግዚአብ ፲፭ ሔር ፡ ተራራ ፡ ይታያል ፡ ይባላል ። የእግዚአብሔር ፡ መልአክም ፡ አብርሃምን ፡ ከሰማይ ፡ ፲፮ ሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡ ጠራው ÷ እንዲህም ፡ አለው ፡— እግዚአብሔር ፡— በራሴ ፡ ማልሁ ፡ ይላል ፤ ይህን ፡ ነገር ፡ አድርገሃልና ÷ አንድ ፡ ልጅህንም ፡ ፲፯ አልከለከልህምና ፡ በእውነት ፡ በረከትን ፡ እባርክሃለሁ ÷ ዘርህንም ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከዋክብትና ፡ በባሕር ፡ ዳር ፡ እንዳለ ፡ አሸዋ ፡ አበዛዋለሁ ፤ ዘርህም ፡ የጠላቶችን ፡ ደጅ ፡ ይወርሳል ፤ ፲፰ የምድር ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉም ፡ በዘርህ ፡ ይባረካሉ ÷ ቃሌን ፡ ሰምተሃልና ። ፲፱ አብርሃምም ፡ ወደ ፡ ብላቴኖቹ ፡ ተመለሰ ÷ ተነሥተውም ፡ ወደ ፡ ቤርሳቤህ ፡ አብረው ፡ ሄዱ ፤ አብርሃምም ፡ በቤርሳቤህ ፡ ተቀመጠ ።

፳ ይህም ፡ ከሆነ ፡ በኋላ ፡ ለአብርሃም ፡ እንዲህ ፡ ተብሎ ፡ ተነገረ ፡— እነሆ ÷ ሚልካ ፡ ደግሞ ፡ ለወንድምህ ፡ ለናኮር ፡ ልጆችን ፡ ወለደች ፤ ፳፩ እነርሱም ፡ በኵሩ ፡ ዑፅ ÷ ወንድሙ ፡ ቡዝ ÷ የአራም ፡ አባት ፡ ቀሙኤል ÷ ፳፪ ከዛት ÷ ሐዞ ÷ ፊልዳሥ ÷ የድላፍ ÷ ባቱኤል ፡ ናቸው ። ፳፫ ባቱኤልም ፡ ርብቃን ፡ ወለደ ፤ እነዚህን ፡ ስምንቱን ፡ ሚልካ ፡ ለአብርሃም ፡ ወንድም ፡ ለናኮር ፡ ወለደች ። ፳፬ ሬሕማ ፡ የሚሉአት ፡ ቁባቱ ፡ ደግሞ ፡ ጥባህን ÷ ገአምን ÷ ተሐሽን ÷ ሞክሳን ፡ ወለደች ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ የሣራም ፡ ዕድሜ ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ። ፪ በቂርያትአርባቅም ፡ ሞተች ፤ እርስዋም ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ያለች ፡ ኬብሮን ፡ ናት ፤ አብርሃምም ፡ ለሣራ ፡ ሊያዝንላትና ፡ ሊያለቅስላት ፡ ተነሣ ። ፫ አብርሃምም ፡ ከሬሳው ፡ አጠገብ ፡ ተነሣ ÷ ለኬጢ ፡ ልጆችም ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ተናገረ ፡— ፬ እኔ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ስደተኛና ፡ መጻተኛ ፡ ነኝ ፤ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ የመቃብር ፡ ርስት ፡ ስጡኝ ÷ ሬሳዬንም ፡ ከፊቴ ፡ ልቅበር ። ፭ የኬጢ ፡ ልጆችም ፡ ለአብርሃም ፡ መለሱ ÷ አሉትም ፡— ፮ ጌታ ፡ ሆይ ÷ ስማን ፤ አንተ ፡ በእኛ ፡ መካከል ፡ ከእግዚአብሔር ፡ አለቃ ፡ ነህ ፤ ከመቃብር ፡ ስፍራችን ፡ በመልካሙ ፡ ቦታ ፡ ሬሳህን ፡ ቅበር ፤ ሬሳህን ፡ ትቀብር ፡ ዘንድ ፡ ከእኛ ፡ መቃብሩን ፡ የሚከለክልህ ፡ የለም ። ፯ አብርሃምም ፡ ተነሣ ÷ ለምድሩ ፡ ሕዝብም ÷ ለኬጢ ፡ ልጆች ÷ ሰገደ ። ፰ እንዲህም ፡ አላቸው ፡— ሬሳዬን ፡ ከፊቴ ፡ እንድቀብር ፡ ከወደዳችሁስ ፡ ስሙኝ ÷ ከሰዓር ፡ ልጅ ፡ ከኤፍሮንም ፡ ለምኑልኝ ፤ ፱ በእርሻው ፡ ዳር ፡ ያለችውን ፡ ድርብ ፡ ክፍል ፡ ያላትን ፡ ዋሻውን ፡ በሙሉ ፡ ዋጋ ፡ በመካከላችሁ ፡ ይስጠኝ ÷ መቃብሩ ፡ የእኔ ፡ ርስት ፡ እንዲሆን ። ፲ ኤፍሮንም ፡ በኬጢ ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ፤ የኬጢ ፡ ሰው ፡ ኤፍሮንም ፡ የኬጢ ፡ ልጆችና ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ የሚገቡ ፡ ሁሉ ፡ ሲሰሙ ፡ ለአብርሃም ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መለሰለት ፡— ፲፩ አይደለም ÷ ጌታዬ ÷ ስማኝ ፤ እርሻውን ፡ ሰጥቼሃለሁ ፡ በእርሱም ፡ ዳር ፡ ያለውን ፡ ዋሻ ፡ ሰጥቼሃለሁ ፤ በወገኔ ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ሰጥቼሃለሁ ፤ ሬሳህን ፡ ቅበር ። ፲፪ አብርሃምም ፡ በአገሩ ፡ ሰዎች ፡ ፊት ፡ ሰገደ ፤ ፲፫ የአገሩ ፡ ሰዎችም ፡ ሲሰሙ ፡ ለኤፍሮን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ተናገረ ፡— ነገሬን ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ፤ የእርሻውን ፡ ዋጋ ፡ እሰጥሃለሁ ፤ አንተም ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ውሰድ ÷ ሬሳዬንም ፡ በዚያ ፡ እቀብራለሁ ። ፲፬ ኤፍሮንም ፡ ለአብርሃም ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መለሰለት ፡— ፲፭ ጌታዬ ፡ ሆይ ÷ እኔን ፡ ስማኝ ፤ የአራት ፡ መቶ ፡ ሰቅል ፡ ዋጋ ፡

ምድር ፡ በእኔና ፡ በአንተ ፡ መካከል ፡ ምንድር ፡ ነው ? ሬሳህንም ፡ ቅበር ። ፲፮ አብርሃምም ፡ የኤፍሮንን ፡ ነገር ፡ ሰማ ፤ አብርሃምም ፡ በኬጢ ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ የነገረውን ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሰቅል ፡ መዝኖ ፡ ለኤፍሮን ፡ ሰጠው ፤ ብሩም ፡ ለመሸጫ ፡ ለመለወጫ ፡ የሚተላለፍ ፡ ነበረ ።

፲፯ በመምሬ ፡ ፊት ፡ ያለው ፡ ባለ ፡ ድርብ ፡ ክፍል ፡ የሆነው ፡ የኤፍሮን ፡ እርሻ ፡ ለአብርሃም ፡ ጸና ፤ እርሻው ፡ በእርሱም ፡ ያለው ፡ ዋሻው ÷ በእርሻውም ፡ ውስጥ ፡ በዙሪያውም ፡ ያለው ፡ እንጨት ፡ ፲፰ ሁሉ ፡ በኬጢ ፡ ልጆችና ፡ በከተማይቱ ፡ በር ፡ በሚገቡ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ለአብርሃም ፡ ርስት ፡ ሆነ ። ፲፱ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ኬብሮን ፡ በምትባል ፡ በመምሬ ፡ ፊት ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ባለው ፡ እርሻ ፡ ባለ ፡ ድርብ ፡ ክፍል ፡ በሆነው ፡ ዋሻ ፡ ውስጥ ፡ አብርሃም ፡ ሚስቱን ፡ ሣራን ፡ ቀበረ ። ፳ እርሻውና ፡ በእርሱ ፡ ያለው ፡ ዋሻው ፡ በኬጢ ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ ለአብርሃም ፡ የመቃብር ፡ ርስት ፡ ሆኖ ፡ ጸና ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ አብርሃምም ፡ ሸመገለ ፡ በዘመኑም ፡ አረጀ ፤ እግዚአብሔርም ፡ አብርሃምን ፡ በሥራው ፡ ሁሉ ፡ ባረከው ። ፪ አብርሃምም ፡ ሎሌውን ፡ የቤቱን ፡ ሽማግሌ ፡ የከብቱን ፡ ሁሉ ፡ አዛዥ ፡ አለው ፡— ፫ እጅህን ፡ ከጭኔ ፡ በታች ፡ አድርግ ÷ እኔም ፡ አብሬ ፡ ከምኖራቸው ፡ ከከነዓን ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ለልጄ ፡ ሚስት ፡ እንዳትወስድለት ፡ በሰማይና ፡ በምድር ፡ አምላክ ፡ በእግዚአብሔር ፡ አምልሃለሁ ፤ ፬ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ አገሬና ፡ ወደ ፡ ተወላጆቼ ፡ ትሄዳለህ ÷ ለልጄ ፡ ለይስሐቅም ፡ ሚስትን ፡ ትወስድለታለህ ። ፭ ሎሌውም ፡— ሴቲቱ ፡ ምናልባት ፡ ወደዚህ ፡ አገር ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ለመምጣት ፡ እንቢ ፡ ያለች ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ልጅህን ፡ ወደ ፡ ወጣህበት ፡ አገር ፡ ልመልሰውን ? አለው ። ፮ አብርሃምም ፡ አለው ፡— ልጄን ፡ ወደዚያ ፡ እንዳትመልስ ፡ ተጠንቀቅ ፤ ፯ ከአባቴ ፡ ቤት ፡ ከተወለድሁበት ፡ ምድርም ፡ ያወጣኝ ÷— ይህችንም ፡ ምድር ፡ እሰጥሃለሁ ፡ ብሎ ፡ የነገረኝና ፡ የማለልኝ ፡ የሰማይ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ÷ እርሱ ፡ መልአኩን ፡ በፊትህ ፡ ይሰድዳል ÷ ከዚያም ፡ ለልጄ ፡ ሚስትን ፡ ትወስዳለህ ። ፰ ሴቲቱም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ለመምጣት ፡ እንቢ ፡ ያለች ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከዚህ ፡ ከቀረብሁህ ፡ መሐላ ፡ ንጹሕ ፡ ነህ ፤ ልጄን ፡ ግን ፡ ወደዚያ ፡ አትመልሰው ። ፱ ሎሌውም ፡ ከጌታው ፡ ከአብርሃም ፡ ጭን ፡ በታች ፡ እጁን ፡ አደረገ ፡ ስለዚሁም ፡ ነገር ፡ ማለለት ።

፲ ሎሌውም ፡ ከጌታው ፡ ግመሎች ፡ መካከል ፡ አሥር ፡ ግመሎችን ፡ ወስዶ ÷ ከጌታውም ፡ ዕቃ ፡ መልካም ፡ መልካሙን ፡ ይዞ ፡ ተነሣ ፤ ተነሥቶም ፡ ወደ ፡ መስጴጦምያ ፡ ወደ ፡ ናኮር ፡ ከተማ ፡ ሄደ ። ፲፩ ሲመሽም ፡ ሴቶች ፡ ውኃ ፡ ሊቀዱ ፡ በሚወጡበት ፡ ጊዜ ፡ ከከተማይቱ ፡ ውጪ ፡ በውኃው ፡ ጕድጓድ ፡ አጠገብ ፡ ግመሎቹን ፡ አስበረከከ ። ፲፪ እንዲህም ፡ አለ ፡— የጌታዬ ፡ የአብርሃም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ÷ እለምንሃለሁ ፤ መንገዴን ፡ ዛሬ ፡ በፊቴ ፡ አቅናልኝ ÷ ለጌታዬም ፡ ለአብርሃም ፡ ምሕረትን ፡ አድርግ ። ፲፫ እነሆ ÷ በዚህ ፡ የውኃ ፡ ምንጭ ፡ አጠገብ ፡ እኔ ፡ ቆሜአለሁ ÷ የዚህችም ፡ ከተማ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ውኃውን ፡ ሊቀዱ ፡ ይመጣሉ ፤ ፲፬ ውኃ ፡ አጠጣ ፡ ዘንድ ፡ እንስራሽን ፡ አዘንብዪ ፡ የምላት ፡ እርስዋም ፡— አንተ ፡ ጠጣ ÷ ግመሎችህን ፡ ደግሞ ፡ አጠጣለሁ ፡ የምትለኝ ፡ ቆንጆ ÷ እርስዋ ፡ ለባሪያህ ፡ ለይስሐቅ ፡ ያዘጋጀሃት ፡ ትሁን ፤ በዚህም ፡ ለጌታዬ ፡ ምሕረትን ፡ እንዳደረግህ ፡ አውቃለሁ ። ፲፭ ይህን ፡ መናገሩንም ፡ ሳይፈጽም ፡ እነሆ ÷ ሚልካ ፡ የወለደችው ፡ የባቱኤል ፡ ልጅ ፡ ርብቃ ፡ እንስራዋን ፡ በጫንቃዋ ፡ ተሸክማ ፡ ወጣች ፤ ሚልካም ፡ የአብርሃም ፡ ወንድም ፡ የናኮር ፡ ሚስት ፡ ናት ። ፲፮ ብላቴናይቱም ፡ መልክዋ ፡ እጅግ ፡ ያማረ ÷ ወንድ ፡ የማያውቃት ፡ ድንግልም ፡ ነበረች ፤ ወደ ፡ ምንጭም ፡ ወረደች ፡ እንስራዋንም ፡ ሞላች ÷ ተመልሳም ፡ ወጣች ። ፲፯ ሎሌውም ፡ ሊገናኛት ፡ ሮጠና ፡— ከእንስራሽ ፡ ጥቂት ፡ ውኃ ፡ ታጠጪኝ ፡ ዘንድ ፡ እለምንሻለሁ ፡ አላት ። ፲፰ እርስዋም ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ÷ ጠጣ ፡ አለችው ፤ ፈጥናም ፡ እንስራዋን ፡ በእጅዋ ፡ አውርዳ ፡ አጠጣችው ። ፲፱ እርሱንም ፡ ካጠጣች ፡ በኋላ ፡— ለግመሎችህ ፡ ደግሞ ፡ ሁሉም ፡ እስኪረኩ ፡ ድረስ ፡ ውኃ ፡ እቀዳለሁ ፡ አለች ። ፳ ፈጥናም ፡ ውኃውን ፡ ከእንስራዋ ፡ በማጠጫው ፡ ውስጥ ፡ ገለበጠችው ÷ ደግሞም ፡ ልትቀዳ ፡ ወደ ፡ ጕድጓዱ ፡ ሮጠች ÷ ለግመሎቹም ፡ ሁሉ ፡ ውኃ ፡ ቀዳች ። ፳፩ ሰውዮውም ፡ ትክ ፡ ብሎ ፡ ይመለከታት ፡ ነበር ፤ እግዚአብሔር ፡ መንገዱን ፡ አቅንቶለት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ወይም ፡ እንዳልሆነ ፡ ለማወቅም ፡ ዝም ፡ አለ ። ፳፪ ግመሎቹም ፡ ከጠጡ ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ ሰውዮው ፡ ግማሽ ፡ ሰቅል ፡ የሚመዝን ፡ የወርቅ ፡ ቀለበት ÷ ለእጆችዋም ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ የሚመዝን ፡ ጥንድ ፡ የወርቅ ፡ አምባር ፡ አወጣ ፤ ፳፫ እንዲህም ፡ አላት ፡— አንቺ ፡ የማን ፡ ልጅ ፡ ነሽ ? እስኪ ፡ ንገሪኝ ፤ በአባትሽ ፡ ቤት ፡ የምናድርበት ፡ ስፍራ ፡ ይገኛልን ? ፳፬ አለችውም ፡— እኔ ፡ ሚልካ ፡ ለናኮር ፡ የወለደችው ፡ የባቱኤል ፡ ልጅ ፡ ነኝ ። ፳፭ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ ገለባና ፡ ገፈራ ፡ የሚበቃ ፡ ያህል ፡ አለ ÷ ለማደሪያም ፡ ደግሞ ፡ ስፍራ ፡ አለን ። ፳፮ ሰውዮውም ፡ አጐንበሰ ÷ ለእግዚአብሔርም ፡ ሰገደ ። ፳፯ እንዲህም ፡ አለ ፡— ቸርነቱንና ፡ እውነቱን ፡ ከጌታዬ ፡ ያላራቀ ፡ የጌታዬ ፡ የአብርሃም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ፤ እኔ ፡ በመንገድ ፡ ሳለሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ጌታዬ ፡ ወንድሞች ፡ ቤት ፡ መራኝ ።

፳፰ ብላቴናይቱም ፡ ሮጠች ÷ ለእናትዋም ፡ ቤት ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ተናገረች ። ፳፱ ለርብቃም ፡ ላባ ፡ የተባለ ፡ ወንድም ፡ ነበራት ፤ ላባም ፡ ወደ ፡ ውጪ ፡ ወደ ፡ ውኃው ፡ ምንጭ ፡ ወደ ፡ ሰውዮው ፡ ሮጠ ። ፴ ቀለበቱንና ፡ አምባሮቹን ፡

በእጎቱ ፡ እጅ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፣ የእኅቱን ፡ የርብ
ቃንም ፡ ነገር ፡— ያ ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡
ያለችውን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፣ እርሱ ፡ ወደዚያ ፡
ሰው ፡ መጣ ፤ እነሆም ፣ በውኃው ፡ ምንጭ ፡
አጠገብ ፡ ከግመሎቹ ፡ ዘንድ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ።
፴፩ ፡ እርሱም ፡ አለው ፡— አንተ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ቡሩክ ፣ ግባ ፤ ስለ ፡ ምን ፡ አንተ ፡ በውጪ ፡
ቆመሃል ? እኔም ፡ ቤቱን ፡ ለግመሎችህም ፡
፴፪ ፡ ስፍራ ፡ አዘጋጅቼአለሁ ። ሰውዮውም ፡ ወደ ፡
ቤት ፡ ገባ ፣ ግመሎቹንም ፡ አራገፈ ፤ ገለባና ፡
ገፈራም ፡ ለግመሎቹ ፡ አቀረበ ፤ እግሩን ፡
ይታጠብ ፡ ዘንድ ፣ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ላሉት ፡
፴፫ ፡ ሰዎች ፡ እግር ፡ ውኃ ፡ አቀረበ ። መብልንም ፡
በፊቱ ፡ አቀረበለት ፤ እርሱ ፡ ግን ፡— ነገሬን ፡
እስክናገር ፡ ድረስ ፡ አልበላም ፡ አለ ። እርሱም ፡—
፴፬ ፡ ተናገር ፡ አለው ። እርሱም ፡ አለ ፡— እኔ ፡ የአ
፴፭ ፡ ብርሃም ፡ ሎሌ ፡ ነኝ ። እግዚአብሔርም ፡ ጌታ
ዬን ፡ እጅግ ፡ ባረከው ፣ አገነነውም ፤ በጎችንና ፡
ላሞችን ፣ ብርንም ፣ ወርቅንም ፣ ወንዶች ፡ ባሪ
ያዎችንና ፡ ሴቶች ፡ ባሪያዎችን ፣ ግመሎችንም ፣
፴፮ ፡ አህዮችንም ፡ ሰጠው ። ሣራም ፡ የጌታዬ ፡
ሚስት ፡ በእርጅናው ፡ ለጌታዬ ፡ ወንድ ፡ ልጅን ፡
፴፯ ፡ ወለደች ፤ የነበረውንም ፡ ሁሉ ፡ ሰጠው ። ጌታ
ዬም ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ አማለኝ ፡— እኔ ፡ ካለሁ
በት ፡ አገር ፡ ከከነዓናውያን ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡
፴፰ ፡ ለልጄ ፡ ሚስትን ፡ አትውሰድ ፡ ነገር ፡ ግን ፡
ወደ ፡ አባቴ ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ወገኔም ፡ ሂድ ፣ ለል
፴፱ ፡ ጄም ፡ ሚስትን ፡ ውሰድለት ። ጌታዬንም ፡—
ሴቲቱ ፡ ምናልባት ፡ ባትከተለኝሳ ? አልሁት ።
፵ ፡ እርሱም ፡ አለኝ ፡— አካሄዴን ፡ በፊቱ ፡ ያደረግ
ሁለት ፡ እግዚአብሔር ፡ መልአኩን ፡ ከአንተ ፡
ጋር ፡ ይልካል ፣ መንገድህንም ፡ ያቀናል ፤ ለል
ጄም ፡ ከወገኖቼ ፡ ከአባቴም ፡ ቤት ፡ ሚስትን ፡
፵፩ ፡ ትወስዳለህ ፤ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከመሐላዬ ፡ ንጹሕ ፡
ነህ ፤ ወደ ፡ ዘመዶቼ ፡ ሄደህ ፡ እነርሱ ፡ ባይሰ
ጡህ ፡ ከማልሁህ ፡ መሐላ ፡ ንጹሕ ፡ ትሆናለህ ።
፵፪ ፡ ዛሬም ፡ ወደ ፡ ውኃው ፡ ምንጭ ፡ መጣሁ ፣ እን
ዲህም ፡ አልሁ ፡— የጌታዬ ፡ የአብርሃም ፡ አም
ላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፣ ዛሬ ፡ የምሄድበ
፵፫ ፡ ትን ፡ መንገዴን ፡ ብታቀናልኝ ፤ እነሆ ፣ እኔ ፡
በውኃው ፡ ምንጭ ፡ ላይ ፡ ቆሜአለሁ ፤ ውኃ ፡
ልትቀዳ ፡ ለምትመጣውም ፡ ቆንጆ ፡— ጥቂት ፡
፵፬ ፡ ውኃ ፡ ከእንስራሽ ፡ አጠጪኝ ፡ ስላት ፣ እርስ
ዋም ፡— አንተ ፡ ጠጣ ፣ ደግሞም ፡ ለግመሎ
ችህ ፡ እቀዳለሁ ፡ የምትለኝ ፣ እግዚአብሔር ፡
ለጌታዬ ፡ ልጅ ፡ ያዘጋጃት ፡ ሴት ፡ እርስዋ ፡ ትሁን ።
፵፭ ፡ እኔም ፡ የልቤን ፡ መናገር ፡ ገና ፡ ሳልፈጽም ፣
እነሆ ፣ ርብቃ ፡ እንስራዋን ፡ በትከሻዋ ፡ ተሸክማ ፡
ወጣች ፣ ወደ ፡ ምንጭም ፡ ወርዳ ፡ ውኃ ፡ ቀዳች ፤
፵፮ ፡ እኔም ፡— እስኪ ፡ አጠጪኝ ፡ አልኋት ። ፈጥ
ናም ፡ እንስራዋን ፡ ከጫንቃዋ ፡ አወረደችና ፡—
አንተ ፡ ጠጣ ፣ ግመሎችህንም ፡ ደግሞ ፡ አጠ
ጣለሁ ፡ አለች ፤ እኔም ፡ ጠጣሁ ፣ ግመሎቼንም ፡
፵፯ ፡ ደግሞ ፡ አጠጣች ። እኔም ፡— አንቺ ፡ የማን ፡
ልጅ ፡ ነሽ ? ብዬ ፡ ጠየቅኋት ። እርስዋም ፡—
ሚልካ ፡ ለናኮር ፡ የወለደችለት ፡ የባቱኤል ፡
ልጅ ፡ ነኝ ፡ አለች ፤ ቀለበትም ፡ አደረግሁላት ፣
፵፰ ፡ ለእጆችዋም ፡ አምባሮች ፡ አደረግሁላት ። በግ
ምባሬም ፡ አጐነበስሁ ፣ ለእግዚአብሔርም ፡ ሰገ
ድሁ ፤ የጌታዬን ፡ የወንድሙን ፡ ልጅ ፡ ለልጁ ፡
እወስድ ፡ ዘንድ ፡ በቀና ፡ መንገድ ፡ የመራኝን ፡
የጌታዬን ፡ የአብርሃምን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብ
፵፱ ፡ ሔርን ፡ አመሰገንሁ ። አሁንም ፡ ቸርነትና ፡
እውነት ፡ ለጌታዬ ፡ ትሠሩ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ንገ
ሩኝ ፤ ይህም ፡ ባይሆን ፡ ንገሩኝ ፣ ወደ ፡ ቀኝ ፡
ወይም ፡ ወደ ፡ ግራ ፡ እል ፡ ዘንድ ።
፶ ፡ ላባና ፡ ባቱኤልም ፡ መለሱ ፡ እንዲህም ፡
አሉ ፡— ነገሩ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ መጥ
ቶአል ፤ ክፉም ፡ በጎም ፡ ልንመልስልህ ፡ አን
፶፩ ፡ ችልም ። ርብቃ ፡ እንኋት ፡ በፊትህ ፡ ናት ፤
ይዘሃት ፡ ሂድ ፣ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡
፶፪ ፡ ለጌታህም ፡ ልጅ ፡ ሚስት ፡ ትሁን ። የአብርሃ
ምም ፡ ሎሌ ፡ ነገራቸውን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡
፶፫ ፡ ምድር ፡ ወድቆ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰገደ ። ሎሌ
ውም ፡ የብርና ፡ የወርቅ ፡ ጌጥ ፡ ልብስም ፡ አወጣ ፣
ለርብቃም ፡ ሰጣት ፤ የከበረ ፡ ስጦታንም ፡ ለወ
፶፬ ፡ ንድምዋና ፡ ለእናትዋ ፡ አቀረበ ። እርሱም ፡
ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ያሉት ፡ በሉ ፡ ጠጡም ፣ ከዚ
ያም ፡ አደሩ ፤ ማልደውም ፡ ተነሡና ፡— ወደ ፡
ጌታዬ ፡ እሄድ ፡ ዘንድ ፡ አሰናብቱኝ ፡ አላቸው ።
፶፭ ፡ ወንድምዋና ፡ እናትዋም ፡— ብላቴናይቱ ፡ አንድ ፡
አሥር ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ እንኳ ፡ ከእኛ ፡ ዘንድ ፡
ትቀመጥ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ትሄዳለች ፡ አሉ ።
፶፮ ፡ እርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡ መንገዴን ፡ አቅን
ቶልኛልና ፡ አታዘግዩኝ ፤ ወደ ፡ ጌታዬ ፡ እሄድ ፡
፶፯ ፡ ዘንድ ፡ አሰናብቱኝ ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡—
ብላቴናይቱን ፡ እንጥራና ፡ ከአፍዋ ፡ እንጠይቅ ፡
፶፰ ፡ አሉ ። ርብቃንም ፡ ጠርተው ፡— ከዚህ ፡ ሰው ፡
ጋር ፡ ትሄጃለሽን ? አሉአት ። እርስዋም ፡—
፶፱ ፡ እሄዳለሁ ፡ አለች ። እኅታቸውንም ፡ ርብቃን ፡
ሞግዚትዋንም ፡ የአብርሃምን ፡ ሎሌና ፡ ሰዎቹ
፷ ፡ ንም ፡ አሰናበቱአቸው ። ርብቃንም ፡ መረቁአ
ትና ፡— አንቺ ፡ እኅታችን ፣ እልፍ ፡ አእላፋት ፡
ሁኚ ፤ ዘርሽም ፡ የጠላቶችን ፡ ደጅ ፡ ይውረስ ፡
አሉአት ።
፷፩ ፡ ርብቃም ፡ ተነሣች ፡ ደንገጥሮችዋም ፣ በግ
መሎችም ፡ ላይ ፡ ተቀምጠው ፡ ያንን ፡ ሰው ፡
ተከተሉት ፤ ሎሌውም ፡ ርብቃን ፡ ተቀብሎ ፡
፷፪ ፡ ሄደ ። ይስሐቅም ፡ ብኤርለሃይሮኢ ፡ በሚሉአት ፡
ምንጭ ፡ መንገድ ፡ መጣ ፤ በአዜብ ፡ ምድር ፡
፷፫ ፡ ተቀምጦ ፡ ነበርና ። ይስሐቅም ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡
በልቡ ፡ እያሰላሰለ ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡ ወጥቶ ፡ ነበር ፤
ዓይኖቹንም ፡ አቀና ፣ እነሆም ፡ ግመሎች ፡
፷፬ ፡ ሲመጡ ፡ አየ ። ርብቃም ፡ ዓይኖችዋን ፡ አቀ
ናች ፣ ይስሐቅንም ፡ አየች ፣ ከግመልም ፡ ወረ
፷፭ ፡ ደች ። ሎሌውንም ፡— ሊገናኘን ፡ በሜዳ ፡ የሚ
መጣ ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ ማን ፡ ነው ? አለችው ።
ሎሌውም ፡— እርሱ ፡ ጌታዬ ፡ ነው ፡ አላት ፤ እር

፷፮ ስዋም ፡ መሸፈኛ ፡ ወስዳ ፡ ተከናነበች ። ሎሌ
ውም ፡ ያደረገውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ለይስሐቅ ፡
፷፯ ነገረው ። ይስሐቅም ፡ ወደ ፡ እናቱ ፡ ወደ ፡ ሣራ ፡
ድንኳን ፡ አገባት ፥ ርብቃንም ፡ ወሰዳት ፥ ሚስ
ትም ፡ ሆነችው ፥ ወደዳትም ፤ ይስሐቅም ፡
ከእናቱ ፡ ሞት ፡ ተጽናና ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

፩ አብርሃምም ፡ ደግሞ ፡ ስምዋ ፡ ኬጡራ ፡ የተባ
፪ ለች ፡ ሚስት ፡ አገባ ። እርስዋም ፡ ዘምራንን ፥
ዮቅሳንን ፥ ሚዳንን ፥ ምድያምን ፥ የስቦቅን ፥ ስዌ
፫ ሕን ፡ ወለደችለት ። ዮቅሳንም ፡ ሳባንና ፡ ድዳንን ፡
ወለደ ። የድዳንም ፡ ልጆች ፡ አሦርያውያን ፥ ለጡ
፬ ሳውያን ፥ ለኡማውያን ፡ ናቸው ። የምድያምም ፡
ልጆች ፡ ጌፌር ፥ ዔፌር ፥ ሄኖኅ ፥ አቢዳዕ ፥ ኤል
ዳዓ ፡ ናቸው ። እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የኬጡራ ፡ ልጆች ፡
፭ ናቸው ። አብርሃምም ፡ የነበረውን ፡ ሁሉ ፡ ለይ
፮ ስሐቅ ፡ ሰጠው ፤ የአብርሃምም ፡ ለነበሩ ፡ ለቁ
ባቶቹ ፡ ልጆች ፡ አብርሃም ፡ ስጦታን ፡ ሰጣቸው ፤
እርሱም ፡ ገና ፡ በሕይወቱ ፡ ሳለ ፡ ከልጁ ፡ ከይስ
ሐቅ ፡ ለይቶ ፡ ወደ ፡ ፀሐይ ፡ መውጫ ፡ ወደ ፡ ምሥ
፯ ራቅ ፡ አገር ፡ ሰደዳቸው ። አብርሃምም ፡ የኖረ
በት ፡ የዕድሜው ፡ ዓመታት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤
፰ መቶ ፡ ሰባ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ኖረ ። አብርሃ
ምም ፡ ነፍሱን ፡ ሰጠ ፥ በመልካም ፡ ሽምግል
ናም ፡ ሞተ ፤ ሸመገለም ፥ ብዙ ፡ ዘመንም ፡
፱ ጠገበ ፤ ወደ ፡ ወገኖቹም ፡ ተከማቸ ። ልጆቹ ፡
ይስሐቅና ፡ እስማኤልም ፡ በመምሬ ፡ ፊት ፡
ለፊት ፡ ባለው ፡ በኬጢያዊ ፡ በሰዓር ፡ ልጅ ፡
በኤፍሮን ፡ እርሻ ፡ ላይ ፡ ባለ ፡ ድርብ ፡ ክፍል ፡
፲ በሆነው ፡ ዋሻ ፡ ውስጥ ፡ ቀበሩት ። አብርሃም ፡
ከኬጢ ፡ ልጆች ፡ የገዛው ፡ እርሻ ፡ ይህ ፡ ነው ፤
አብርሃምና ፡ ሚስቱ ፡ ሣራ ፡ ከዚያ ፡ ተቀበሩ ።
፲፩ አብርሃምም ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡
ልጁን ፡ ይስሐቅን ፡ ባረከው ፤ ይስሐቅም ፡ ብኤ
ርለሃይሮኢ ፡ ተብሎ ፡ በሚጠራው ፡ ምንጭ ፡
አጠገብ ፡ ኖረ ።
፲፪ የሣራ ፡ ባሪያ ፡ ግብፃዊቱ ፡ አጋር ፡ ለአብርሃም ፡
የወለደችው ፡ የአብርሃም ፡ ልጅ ፡ የእስማኤል ፡
፲፫ ትውልድ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የእስማኤልም ፡ የል
ጆቹ ፡ ስም ፡ በየስማቸውና ፡ በየትውልዳቸው ፡
እንዲህ ፡ ነው ፤ የእስማኤል ፡ የበኵር ፡ ልጁ ፡
፲፬ ነባዮት ፥ ቄዳር ፥ ነብዳኤል ፥ መብሳም ፥ ማስማዕ ፥
፲፭ ዱማ ፥ ማሣ ፥ ኩዳን ፥ ቴማን ፥ ኢጡር ፥ ናፌስ ፥
፲፮ ቄድማ ። የእስማኤል ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፥
ስማቸውም ፡ በየመንደራቸውና ፡ በየሰፈራቸው ፡
ይኸው ፡ ነው ፤ በየወገናቸውም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡
፲፯ አለቆች ፡ ናቸው ። እስማኤልም ፡ የኖረበት ፡ የዕ
ድሜው ፡ ዘመን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡
ነው ፤ ነፍሱን ፡ ሰጠ ፡ ሞተም ፤ ወደ ፡ ወገኖቹም ፡
፲፰ ተከማቸ ። መኖሪያቸውም ፡ ከኤውላጥ ፡ አን
ሥቶ ፡ በግብፅ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ እስከምትገኝ ፡
እስከ ፡ ሱር ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ አሦር ፡ በምትወስ
ደው ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ ነበረ ፤ እንዲህም ፡ በወ
ንድሞቹ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ተቀመጠ ።
፲፱ የአብርሃም ፡ ልጅ ፡ የይስሐቅ ፡ ትውልድም ፡
ይህ ፡ ነው ፤ አብርሃም ፡ ይስሐቅን ፡ ወለደ ፤
፳ ይስሐቅም ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ሲሆነው ፡ ርብቃን ፡
አገባ ፤ እርስዋም ፡ በሁለት ፡ ወንዞች ፡ መካከል ፡
ያለ ፡ የሶርያዊው ፡ የባቱኤል ፡ ልጅና ፡ የሶርያ
፳፩ ዊው ፡ የላባ ፡ እኅት ፡ ናት ። ይስሐቅም ፡ ስለ ፡
ሚስቱ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸለየ ፥ መካን ፡
ነበረችና ፤ እግዚአብሔርም ፡ ተለመነው ፥ ርብ
፳፪ ቃም ፡ ሚስቱ ፡ ፀነሰች ። ልጆችም ፡ በሆድዋ ፡
ውስጥ ፡ ይገፉፉ ፡ ነበር ፤ እርስዋም ፡— እንዲህ ፡
ከሆነ ፡ ይህ ፡ ለእኔ ፡ ምኔ ፡ ነው ? አለች ። ከእ
ግዚአብሔርም ፡ ትጠይቅ ፡ ዘንድ ፡ ሄደች ።
፳፫ እግዚአብሔርም ፡ አላት ፡— ሁለት ፡ ወገኖች ፡
በማኅፀንሽ ፡ ናቸው ፥ ሁለቱም ፡ ሕዝብ ፡ ከሆ
ድሽ ፡ ይከፈላሉ ፤ ሕዝብም ፡ ከሕዝብ ፡ ይበረ
፳፬ ታል ፤ ታላቁም ፡ ለታናሹ ፡ ይገዛል ። ትወልድ ፡
ዘንድ ፡ ዘመንዋ ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜም ፥ እነሆ ፥
፳፭ በማኅፀንዋ ፡ መንታ ፡ ነበሩ ። በፊትም ፡ የወ
ጣው ፡ ቀይ ፡ ነበረ ፥ ሁለንተናውም ፡ ጠጕር ፡
፳፮ ለብሶ ፡ ነበር ፤ ስሙም ፡ ዔሳው ፡ ተባለ ። ከዚ
ያም ፡ በኋላ ፡ ወንድሙ ፡ ወጣ ፥ በእጁም ፡ የዔ
ሳውን ፡ ተረከዝ ፡ ይዞ ፡ ነበር ፤ ስሙም ፡ ያዕ
ቆብ ፡ ተባለ ። እርስዋ ፡ ልጆችን ፡ በወለደቻ
ቸው ፡ ጊዜ ፡ ይስሐቅ ፡ ስድሳ ፡ ዓመት ፡ ሆኖት ፡
ነበር ።
፳፯ ብላቴኖቹም ፡ አደጉ ፤ ዔሳውም ፡ አደን ፡ የሚ
ያውቅ ፡ የበረሃ ፡ ሰው ፡ ሆነ ፤ ያዕቆብ ፡ ግን ፡
ጭምት ፡ ሰው ፡ ነበረ ፥ በድንኳንም ፡ ይቀመጥ ፡
፳፰ ነበር ። ይስሐቅም ፡ ዔሳውን ፡ ይወድ ፡ ነበር ፥
ከአደነው ፡ ይበላ ፡ ነበርና ፤ ርብቃ ፡ ግን ፡ ያዕ
፳፱ ቆብን ፡ ትወድ ፡ ነበረች ። ያዕቆብም ፡ ወጥ ፡
፴ ሠራ ፤ ዔሳውም ፡ ደክሞ ፡ ከበረሃ ፡ ገባ ፤ ዔሳ
ውም ፡ ያዕቆብን ፡— ከዚህ ፡ ከቀዩ ፡ ወጥ ፡ አብ
ላኝ ፥ እኔ ፡ እጅግ ፡ ደክሜአለሁና ፡ አለው ፤ ስለ
፴፩ ዚህ ፡ ስሙ ፡ ኤዶም ፡ ተባለ ። ያዕቆብም ፡—
በመጀመሪያ ፡ ብኵርናህን ፡ ሽጥልኝ ፡ አለው ።
፴፪ ዔሳውም ፡— እነሆ ፥ እኔ ፡ ልሞት ፡ ነኝ ፤ ይህች ፡
፴፫ ብኵርና ፡ ለምኔ ፡ ናት ? አለ ። ያዕቆብም ፡—
እስኪ ፡ በመጀመሪያ ፡ ማልልኝ ፡ አለው ። ማለ
ለትም ፤ ብኵርናውንም ፡ ለያዕቆብ ፡ ሸጠ ።
፴፬ ያዕቆብም ፡ ለዔሳው ፡ እንጀራና ፡ የምስር ፡ ወጥ ፡
ሰጠው ፤ በላ ፥ ጠጣ ፥ ተነሥቶም ፡ ሄደ ፤ እን
ዲሁም ፡ ዔሳው ፡ ብኵርናውን ፡ አቃለላት ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩ በምድርም ፡ ቀድሞ ፡ በአብርሃም ፡ ዘመን ፡
ከሆነው ፡ ራብ ፡ ላይ ፡ ራብ ፡ ሆነ ፤ ይስሐቅም ፡
ወደ ፡ ፍልስጥኤም ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ አቢሜሌክ ፡
፪ ወደ ፡ ጌራራ ፡ ሄደ ። እግዚአብሔር ፡ ተገለጠ
ለት ፥ እንዲህም ፡ አለው ፡— ወደ ፡ ግብፅ ፡ አት
ውረድ ፥ እኔ ፡ በምልህ ፡ ምድር ፡ ተቀመጥ ፡
፫ እንጂ ። በዚህች ፡ ምድር ፡ ተቀመጥ ፥ ከአንተ ፡
ጋርም ፡ እሆናለሁ ፥ እባርክሃለሁም ፤ እነዚህን ፡

ምድሮች ፡ ሁሉ ፡ ለአንተም ፡ ለዘርህም ፡ እሰጣ
ለሁና ፤ ለአባትህ ፡ ለአብርሃም ፡ የማልሁለትንም ፡
፬ መሐላ ፡ አጸናለሁ ። ዘርህንም ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡
ከዋክብት ፡ አበዛለሁ ፤ እነዚህንም ፡ ምድሮች ፡
ሁሉ ፡ ለዘርህ ፡ እሰጣለሁ ፤ የምድርም ፡ አሕ
፭ ዛብ ፡ ሁሉ ፡ በዘርህ ፡ ይባረካሉ ፤ አብርሃም ፡
ቃሌን ፡ ሰምቶአልና ፤ ፍርዴን ፡ ትእዛዜን ፡ ሥር
፮ ዓቴን ፡ ሕጌንም ፡ ጠብቆአልና ። ይስሐቅም ፡
፯ በጌራራ ፡ ተቀመጠ ። የዚያም ፡ ስፍራ ፡ ሰዎች ፡
ስለ ፡ ሚስቱ ፡ ጠየቁት ፤ እርሱም ፦ እኅቴ ፡
ናት ፡ አለ ፤ የዚህ ፡ ስፍራ ፡ ሰዎች ፡ ለርብቃ ፡
ሲሉ ፡ እንዳይገድሉኝ ፡ ብሎ ፡ ሚስቴ ፡ ናት ፡
ማለትን ፡ ፈርቶአልና ፤ እርስዋ ፡ ውብ ፡ ነበረ
፰ ችና ። በዚያም ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ ከተቀመጠ ፡ በኋላ ፡
የፍልስጥኤም ፡ ንጉሥ ፡ አቢሜሌክ ፡ በመስኮት ፡
ሆኖ ፡ ጐበኘ ፤ ይስሐቅም ፡ ሚስቱን ፡ ርብቃን ፡
፱ ሲዳራት ፡ አየ ። አቢሜሌክም ፡ ይስሐቅን ፡
ጠራ ፤ እንዲህም ፡ አለው ፦ እነሆ ፡ ሚስትህ ፡
ናት ፤ እንዴትስ ፡ እርስዋን ፦ እኅቴ ፡ ናት ፡
አልህ ? ይስሐቅም ፦ በእርስዋ ፡ ምክንያት ፡
፲ እንዳልሞት ፡ ብዬ ፡ ነው ፡ አለው ። አቢሜሌ
ክም ፡ አለ ፦ ይህ ፡ ያደረግህብን ፡ ምንድር ፡
ነው ? ከሕዝብ ፡ አንዱ ፡ ከሚስትህ ፡ ጋር
ሊተኛ ፡ ጥቂት ፡ በቀረው ፡ ነበር ፤ ኃጢአት
፲፩ ንም ፡ ልታመጣብን ፡ ነበር ። አቢሜሌክም ፡
ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፦ ይህን ፡ ሰው ፡ ሚስቱንም
የሚነካ ፡ ሞትን ፡ ይሙት ፡ ብሎ ፡ አዘዘ ።

፲፪ ይስሐቅም ፡ በዚያች ፡ ምድር ፡ ዘርን ፡ ዘራ ፤
በዚያች ፡ ዓመትም ፡ መቶ ፡ እጥፍ ፡ አገኘ ፤ እግ
፲፫ ዚአብሔርም ፡ ባረከው ። ባለ ፡ ጠጋ ፡ ሰውም ፡
ሆነ ፤ እጅግ ፡ እስኪበልጥ ፡ ድረስም ፡ እየጨ
፲፬ መረ ፡ ይበዛ ፡ ነበር ፤ የበግና ፡ የላም ፡ ከብትም ፡
ሎሌዎችም ፡ እጅግ ፡ በዙለት ፤ የፍልስጥኤም ፡
፲፭ ሰዎች ፡ ቀኑበት ። በአባቱ ፡ በአብርሃም ፡ ዘመን ፡
የአባቱ ፡ ሎሌዎች ፡ የማሱአቸውን ፡ ጉድጓዶች ፡
ሁሉ ፡ የፍልስጥኤም ፡ ሰዎች ፡ ደፈኑአቸው ፤
፲፮ አፈርንም ፡ ሞሉባቸው ። አቢሜሌክም ፡ ይስ
ሐቅን ፦ ከእኛ ፡ ተለይተህ ፡ ሂድ ፤ ከእኛ
፲፯ ይልቅ ፡ እጅግ ፡ በርትተሃልና ፡ አለው ። ይስሐ
ቅም ፡ ከዚያ ፡ ሄደ ፤ በጌራራም ፡ ሸለቆ ፡ ሰፍሮ
በዚያ ፡ ተቀመጠ ።

፲፰ ይስሐቅም ፡ በአባቱ ፡ በአብርሃም ፡ ዘመን ፡
ቈፍረዋቸው ፡ የነበሩትን ፡ የውኃ ፡ ጉድጓዶች ፡
ደግሞ ፡ አስቈፈረ ፤ አብርሃም ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡
የፍልስጥኤም ፡ ሰዎች ፡ ደፍነዋቸው ፡ ነበሩና ፤
አባቱም ፡ ይጠራቸው ፡ በነበረው ፡ ስም ፡ ጠራ
፲፱ ቸው ። የይስሐቅ ፡ ሎሌዎችም ፡ በሸለቆው ፡
ውስጥ ፡ ቈፈሩ ፤ በዚያም ፡ የሚመነጭ ፡ የውኃ ፡
፳ ጉድጓድ ፡ አገኙ ። የጌራራ ፡ አገር ፡ እረኞች ፡
ከይስሐቅ ፡ እረኞች ፡ ጋር ፦ ውኃው ፡ የእኛ ፡
ነው ፡ ሲሉ ፡ ተከራከሩ ፤ የዚያችንም ፡ ጉድጓድ ፡
ስም ፡ ኤሴቅ ፡ ብሎ ፡ ጠራት ፤ ለእርስዋ ፡ ሲሉ ፡
፳፩ ተጣልተዋልና ። ሌላ ፡ ጉድጓድም ፡ ማሱ ፤ ስለ ፡
እርስዋም ፡ ደግሞ ፡ ተጣሉ ፤ ስምዋንም ፡ ስጥና ፡
ብሎ ፡ ጠራት ። ከዚያም ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ ፳፪
ሌላ ፡ ጉድጓድ ፡ አስቈፈረ ፤ ስለ ፡ እርስዋም ፡
አልተጣሉም ፤ ስምዋንም ፡ ርኆቦት ፡ ብሎ ፡
ጠራት ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፦ አሁን ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ አሰፋልን ፤ በምድርም ፡ እንበዛለን ።

፳፫ ፡ ፳፬ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ቤርሳቤህ ፡ ወጣ ። በዚያችም ፡
ሌሊት ፡ እግዚአብሔር ፡ ተገለጠለት ፤ እንዲ
ህም ፡ አለው ፦ እኔ ፡ የአባትህ ፡ የአብርሃም ፡
አምላክ ፡ ነኝ ፤ አትፍራ ፤ እኔ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡
ነኝና ፤ እባርክሃለሁ ፤ ስለ ፡ ባሪያዬ ፡ ስለ ፡ አብ
ርሃም ፡ ዘርህን ፡ አበዛለሁ ። ፳፭ በዚያም ፡ መሠዊ
ያን ፡ ሠራ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ ጠራ ፤
በዚያም ፡ ድንኳን ፡ ተከለ ፤ የይስሐቅም ፡ ሎሌ
ዎች ፡ በዚያ ፡ ጉድጓድ ፡ ማሱ ።

፳፮ አቢሜሌክና ፡ የሙሽራው ፡ ወዳጅ ፡ አኮዘት ፡
የሠራዊቱም ፡ አለቃ ፡ ፊኮል ፡ ከጌራራ ፡ ወደ ፡
እርሱ ፡ ሄዱ ። ፳፯ ይስሐቅም ፦ ለምን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡
መጣችሁ ? እናንተ ፡ ጠልታችሁኛል ፤ ከእናን
ተም ፡ ለይታችሁ ፡ አሳድዳችሁኛል ፡ አላቸው ።
፳፰ ፡ ፳፱ እነርሱም ፡ አሉት ፦ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡
ጋር ፡ እንዳለ ፡ በእርግጥ ፡ አየን ፤ ስለዚህም ፦
በእኛና ፡ በአንተ ፡ መካከል ፡ መሐላ ፡ ይሁን ፤ እኛ ፡
አንተን ፡ እንዳልነካንህ ፤ በጎነትንም ፡ ብቻ ፡ እን
ዳሳየንህ ፤ በደኅናም ፡ እንደ ፡ ሰደድንህ ፤ አን
ተም ፡ ክፉ ፡ እንዳትሠራብን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ከአ
ንተ ፡ ጋር ፡ እናድርግ ፡ አልን ፤ አንተ ፡ አሁን ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተባረክህ ፡ ነህ ። ፴ ይስ
ሐቅም ፡ ማዕድ ፡ አቀረበላቸው ፤ በሉም ፡
ጠጡም ። ፴፩ ማልደውም ፡ ተነሡ ፤ እርስ ፡ በር
ሳቸውም ፡ ተማማሉ ፤ ይስሐቅም ፡ አሰናበታ
ቸው ፤ ከእርሱም ፡ ወጥተው ፡ በደኅና ፡ ሄዱ ።
፴፪ በዚያም ፡ ቀን ፡ የይስሐቅ ፡ ሎሌዎች ፡ መጡ ፤
ስለ ፡ ቈፈሩአትም ፡ ጉድጓድ ፦ ውኃ ፡ አገኘን ፡
ብለው ፡ ነገሩት ። ፴፫ ስምዋንም ፡ ሳቤህ ፡ ብሎ ፡
ጠራት ፤ ስለዚህም ፡ የከተማይቱ ፡ ስም ፡ እስከ ፡
ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ቤርሳቤህ ፡ ነው ።

፴፬ ዔሳውም ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ሲሆነው ፡ የኬጢ
ያዊ ፡ የብኤሪን ፡ ልጅ ፡ ዮዲትን ፤ የኬጢያዊ ፡
የኤሎንን ፡ ልጅ ፡ ቤሴሞትንም ፡ ሚስቶች ፡
አድርጎ ፡ አገባ ፤ ፴፭ እነርሱም ፡ የይስሐቅንና ፡ የር
ብቃን ፡ ልብ ፡ ያሳዝኑ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

፩ ይስሐቅ ፡ ሸምግሎ ፡ ዓይኖቹ ፡ ከማየት ፡ በፈ
ዘዙ ፡ ጊዜ ፡ ታላቁን ፡ ልጁን ፡ ዔሳውን ፡ ጠርቶ ፦
ልጄ ፡ ሆይ ፡ አለው ፤ እርሱም ፦ እነሆ ፡ አለሁ ፡
አለው ። ፪ እርሱም ፡ አለው ፦ እነሆ ፡ እኔ ፡
አረጀሁ ፤ የምሞትበትን ፡ ቀን ፡ አላውቅም ።
፫ አሁንም ፡ ማደኛህን ፡ የፍላጻህን ፡ አፎትና ፡ ቀስ
ትህን ፡ ውሰድ ፤ ወደ ምድረ ፡ በዳም ፡ ውጣ ፤
፬ አደንም ፡ አድንልኝ ፤ ሳልሞትም ፡ ነፍሴ ፡ እንድ
ትባርክህ ፡ የጣፈጠ ፡ መብል ፡ እኔ ፡ እንደምወ
ደው ፡ አዘጋጅተህ ፡ አበላ ፡ ዘንድ ፡ አምጣልኝ ።
፭ ርብቃም ፡ ይስሐቅ ፡ ለልጁ ፡ ለዔሳው ፡ ሲነ

ግር ፡ ትሰማ ፡ ነበር ። ዔሳውም ፡ አደን ፡ አድኖ ፡
፮ ሊያመጣ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሄደ ። ርብቃም ፡
ልጅዋን ፡ ያዕቆብን ፡ እንዲህ ፡ አለችው ፦ እነሆ ÷
፯ አባትህ ፡ ለወንድምህ ፡ ለዔሳው ፦ አደን ፡ አድ
ነህ ፡ አምጣልኝ ÷ ሳልሞትም ፡ በልቼ ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ ፊት ፡ እንድባርክህ ፡ የጣፈጠ ፡ መብል ፡
፰ አድርግልኝ ፡ ብሎ ፡ ሲነግረው ፡ ሰማሁ ። አሁ
ንም ÷ ልጄ ፡ ሆይ ÷ እኔ ፡ በማዝዝህ ፡ ነገር ፡ ስማኝ ፤
፱ ወደ ፡ መንጋ ፡ ሄደህ ፡ ሁለት ፡ መልካካም ፡ ጠቦ
ቶች ፡ አምጣልኝ ፤ እነርሱንም ፡ ጣፋጭ ፡
መብል ፡ ለአባትህ ፡ እንደሚወደው ፡ አደርጋ
፲ ለሁ ፤ ለአባትህም ÷ ሳይሞት ፡ እንዲባርክህ ÷
፲፩ ይብላ ፡ ዘንድ ፡ ታገባለታለህ ። ያዕቆብም ፡ ርብ
ቃን ፡ እናቱን ፡ አላት ፦ እነሆ ፤ ዔሳው ፡ ወን
ድሜ ፤ ጠጕራም ፡ ሰው ፡ ነው ÷ እኔ ፡ ግን ፡
፲፪ ለስላሳ ፡ ነኝ ፤ ምናልባት ፡ አባቴ ፡ ቢዳስሰኝ ፡
በፊቱ ፡ እንደሚዘብት ፡ እሆናለሁ ፤ መርገም
ንም ፡ በላዬ ፡ አመጣለሁ ÷ በረከትን ፡ አይደለም ።
፲፫ እናቱም ፡ አለችው ፦ ልጄ ፡ ሆይ ÷ መርገምህ ፡
በእኔ ፡ ላይ ፡ ይሁን ፤ ቃሌን ፡ ብቻ ፡ ስማኝ ፤ ሂድና ፡
፲፬ አምጣልኝ ። ሄዶም ፡ አመጣ ÷ ለእናቱም ፡
ሰጣት ፤ እናቱም ፡ የጣፈጠውን ፡ መብል ፡ አባቱ ፡
፲፭ እንደሚወደው ፡ አደረገች ። ርብቃም ፡ ከእር
ስዋ ፡ ዘንድ ፡ በቤት ፡ የነበረችውን ፡ የታላቁን ፡
ልጅዋን ፡ የዔሳውን ፡ መልካሙን ፡ ልብስ ፡ አመ
ጣች ÷ ታናሹን ፡ ልጅዋን ፡ ያዕቆብንም ፡ አለበ
፲፮ ሰችው ፤ የጠቦቶችንም ፡ ለምድ ፡ በእጆቹና ፡
፲፯ በለስላሳው ፡ አንገቱ ፡ ላይ ፡ አደረገች ፤ የሠራች
ውን ፡ ጣፋጭ ፡ መብልና ፡ እንጀራውን ፡ ለል
ጅዋ ፡ ለያዕቆብ ፡ በእጁ ፡ ሰጠችው ።
፲፰ ወደ ፡ አባቱም ፡ ገብቶ ፦ አባቴ ፡ ሆይ ፡ አለው ፡
እርሱም ፦ እነሆኝ ፤ ልጄ ፡ ሆይ ÷ አንተ ፡ ማን ፡
፲፱ ነህ ? አለ ። ያዕቆብም ፡ አባቱን ፡ አለው ፦
የበኵር ፡ ልጅህ ፡ እኔ ፡ ዔሳው ፡ ነኝ ፤ እንዳዘዝ
ኸኝ ፡ አደረግሁ ፤ ነፍስህ ፡ ትባርከኝ ፡ ዘንድ ፡
፳ ቀና ፡ በልና ፡ ተቀመጥ ÷ ካደንሁትም ፡ ብላ ። ይስ
ሐቅም ፡ ልጁን ፦ ልጄ ፡ ሆይ ÷ እንዴት ፡ ፈጥ
ነህ ፡ አገኘኸው ? አለው ። እርሱም ፦ እግዚ
አብሔር ፡ አምላክህ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ስለ ፡ አቀረ
፳፩ በው ፡ ነው ፡ አለ ። ይስሐቅም ፡ ያዕቆብን ፦
ልጄ ፡ ሆይ ÷ አንተ ፡ ልጄ ፡ ዔሳው ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡
ወይም ፡ እንዳልሆንህ ፡ እዳስስህ ፡ ዘንድ ፡ ቅረ
፳፪ በኝ ፡ አለው ። ያዕቆብም ፡ ወደ ፡ አባቱ ፡ ወደ ፡
ይስሐቅ ፡ ቀረበ ፤ ዳሰሰውም ÷ እንዲህም ፦
ይህ ፡ ድምፅ ፡ የያዕቆብ ፡ ድምፅ ፡ ነው ÷ እጆች ፡
፳፫ ግን ፡ የዔሳው ፡ እጆች ፡ ናቸው ፡ አለው ። እር
ሱም ፡ አላወቀውም ፡ ነበር ፤ እጆቹ ፡ እንደ ፡ ወን
ድሙ ፡ እንደ ፡ ዔሳው ፡ እጆች ፡ ጠጕራም ፡
፳፬ ነበሩና ፤ ስለዚህም ፡ ባረከው ። አለውም ፦
አንተ ፡ ልጄ ፡ ዔሳው ፡ ነህን ? እርሱም ፦ እኔ ፡
፳፭ ነኝ ፡ አለ ። እርሱም ፦ ከልጄ ፡ አደን ፡ እንድ
በላና ፡ ነፍሴ ፡ እንድትባርክህ ፡ አቅርብልኝ ፡ አለ ።
አቀረበለትም ÷ በላም ፤ የወይን ፡ ጠጅ ፡ አመ
፳፮ ጣለት ÷ እርሱም ፡ ጠጣ ። አባቱ ፡ ይስሐቅም ፦
ልጄ ፡ ሆይ ÷ ወደ ፡ እኔ ፡ ቅረብ ፡ ሳመኝም ፡
፳፯ አለው ። ወደ ፡ እርሱም ፡ ቀረበ ÷ ሳመውም ፤ የል
ብሱንም ፡ ሽታ ፡ አሸተተ ÷ ባረከውም ÷ እን
ዲህም ፡ አለ ፦ የልጄ ፡ ሽታ ፡ እግዚአብሔር ፡
፳፰ እንደ ፡ ባረከው ፡ እርሻ ፡ ሽታ ፡ ነው ፤ እግዚአብ
ሔርም ፡ ከሰማይ ፡ ጠል ፡ ከምድርም ፡ ስብ ፡
የእህልንም ፡ የወይንንም ፡ ብዛት ፡ ይስጥህ ፤
፳፱ አሕዛብ ፡ ይገዙልህ ፡ ሕዝብም ፡ ይስገዱልህ ፤
ለወንድሞችህ ፡ ጌታ ፡ ሁን ÷ የእናትህም ፡ ልጆች ፡
ይስገዱልህ ፤ የሚረግምህ ፡ እርሱ ፡ ርጉም ፡
ይሁን ÷ የሚባርክህም ፡ ቡሩክ ፡ ይሁን ።

፴ ይስሐቅም ፡ ያዕቆብን ፡ ባርኮ ፡ ከፈጸመ ፡ በኋላ ÷
ያዕቆብም ፡ ከአባቱ ፡ ከይስሐቅ ፡ ፊት ፡ ከወጣ ፡
በኋላ ÷ ወዲያው ፡ በዚያው ፡ ጊዜ ፡ ዔሳው ፡ ከአ
፴፩ ደኑ ፡ መጥቶ ፡ ገባ ። እርሱም ፡ ደግሞ ፡ ጣፋጭ ፡
መብል ፡ አዘጋጀ ÷ ለአባቱም ፡ አገባ ፤ አባቱ
ንም ፦ አባቴ ፡ ይነሣ ÷ ነፍስህም ፡ ትባርከኝ ፡
ዘንድ ፡ ከልጁ ፡ አደን ፡ ይብላ ፡ አለው ።
፴፪ አባቱ ፡ ይስሐቅም ፦ አንተ ፡ ማን ፡ ነህ ? አለው ።
እርሱም ፦ እኔ ፡ የበኵር ፡ ልጅህ ፡ ዔሳው ፡ ነኝ ፡
፴፫ አለው ። ይስሐቅም ፡ እጅግ ፡ ደነገጠ ፡ እንዲህም ፡
አለ ፦ ያደነውን ፡ አደን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ያመጣ ፡
ማን ፡ ነው ? አንተ ፡ ሳትመጣም ፡ ከሁሉ ፡ በላሁ ፡
ባረክሁትም ፤ እርሱም ፡ የተባረከ ፡ ሆኖ ፡ ይኖ
፴፬ ራል ። ዔሳውም ፡ የአባቱን ፡ ቃል ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡
ታላቅ ፡ እጅግም ፡ መራራ ፡ ጩኸት ፡ ጮኸ ÷
አባቱንም ፦ አባቴ ፡ ሆይ ÷ እኔንም ፡ ደግሞ ፡
፴፭ ባርከኝ ፡ አለው ። እርሱም ፦ ወንድምህ ፡ በተ
ንኰል ፡ ገብቶ ፡ በረከትህን ፡ ወሰደብህ ፡ አለ ።
፴፮ እርሱም ፡ አለ ፦ በእውነት ፡ ስሙ ፡ ያዕቆብ ፡
ተባለ ÷ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ አሰናክሎኛልና ፤ ብኵር
ናዬን ፡ ወሰደ ÷ አሁንም ፡ እነሆ ፡ በረከቴን ፡
ወሰደ ። ደግሞም ፦ ለእኔ ፡ በረከትን ፡ አላስቀ
፴፯ ረህልኝምን ? አለ ። ይስሐቅም ፡ መለሰ ፡ ዔሳው
ንም ፡ አለው ፦ እነሆ ÷ ጌታህ ፡ አደረግሁት ÷
ወንድሞቹንም ፡ ሁሉ ፡ ለእርሱ ፡ ተገዦች ፡
ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ሰጠሁት ÷ በእህልም ፡ በወይንም ፡
አበረታሁት ፤ ለአንተ ፡ ግን ÷ ልጄ ፡ ሆይ ÷ ምን ፡
፴፰ ላድርግ ? ዔሳውም ፡ አባቱን ፡ አለው ፦ አባቴ ፡
ሆይ ÷ በረከትህ ፡ አንዲት ፡ ብቻ ፡ ናትን ? አባቴ ፡
ሆይ ÷ እኔንም ፡ ደግሞ ፡ ባርከኝ ። ዔሳውም ፡
፴፱ ቃሉን ፡ አንሥቶ ፡ አለቀሰ ። አባቱ ፡ ይስሐቅም ፡
መለሰ ፡ አለውም ፦ እነሆ ÷ መኖሪያህ ፡ ከም
ድር ፡ ስብ ፡ ከላይ ፡ ከሚገኝ ፡ ከሰማይም ፡ ጠል ፡
፵ ይሆናል ፤ በሰይፍህም ፡ ትኖራለህ ÷ ለወንድም
ህም ፡ ትገዛለህ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በተቃወምኸው ፡
ጊዜ ፡ ቀንበሩን ፡ ከአንገትህ ፡ ትጥላለህ ።

፵፩ ዔሳውም ፡ አባቱ ፡ ስለ ፡ ባረከው ፡ በያዕቆብ ፡
ቂም ፡ ያዘበት ፤ ዔሳውም ፡ በልቡ ፡ አለ ፦ ለአ
ባቴ ፡ የልቅሶ ፡ ቀን ፡ ቀርቦአል ÷ ከዚያም ፡ በኋላ ፡
፵፪ ወንድሜን ፡ ያዕቆብን ፡ እገድለዋለሁ ። ለርብ
ቃም ፡ ይህ ፡ የታላቁ ፡ ልጅዋ ፡ የዔሳው ፡ ቃል ፡
ደረሰላት ፤ ታናሹን ፡ ልጅዋን ፡ ያዕቆብንም ፡ አስ
ጠርታ ፡ አስመጣችው ÷ አለችውም ፦ እነሆ ÷

ወንድምህ ፡ ዔሳው ፡ ሊገድልህ ፡ ይፈቅዳል ። ፵፫ አሁንም ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ቃሌን ፡ ስማ ፤ ተነሣና ፡ ወደ ፡ ካራን ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ ወንድሜ ፡ ወደ ፡ ፵፬ ላባ ፡ ሂድ ፤ በእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ጥቂት ፡ ቀን ፡ ተቀመጥ ፥ የወንድምህ ፡ ቍጣ ፡ እስኪበርድ ፡ ፵፭ ድረስ ፤ የወንድምህ ፡ ቍጣ ፡ ከአንተ ፡ እስኪመለስ ፡ ድረስ ፥ ያደረግህበትንም ፡ እስኪረሳው ፡ ድረስ ፤ ከዚያም ፡ ልኬ ፡ አስመጣሃለሁ ፤ በአንድ ፡ ቀን ፡ ሁለታችሁን ፡ ለምን ፡ አጣለሁ ?

፵፮ ርብቃም ፡ ይስሐቅን ፡ አለችው ፡— ከኬጢ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ የተነሣ ፡ ሕይወቴን ፡ ጠላሁት ፤ ያዕቆብ ፡ ከዚህ ፡ አገር ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ሚስትን ፡ የሚያገባ ፡ ከሆነ ፡ በሕይወት ፡ መኖር ፡ ለምኔ ፡ ነው ?

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

፩ ይስሐቅም ፡ ያዕቆብን ፡ ጠራው ፥ ባረከውም ፥ እንዲህ ፡ ብሎም ፡ አዘዘው ፡— ከከነዓናውያን ፡ ፪ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ሚስትን ፡ አታግባ ፤ ተነሣና ፡ ወደ ፡ እናትህ ፡ አባት ፡ ወደ ፡ በቱኤል ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ሁለቱ ፡ ወንዞች ፡ መካከል ፡ ሂድ ፤ ከዚያም ፡ ከእናትህ ፡ ወንድም ፡ ከላባ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ሚስ ፫ ትን ፡ አግባ ። ሁሉን ፡ የሚችል ፡ አምላክም ፡ ለብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ጉባኤ ፡ እንድትሆን ፡ ይባርክህ ፥ ፬ ያፍራህ ፥ ያብዛህ ፤ ስደተኛ ፡ ሆነህ ፡ የተቀመጥህበትን ፡ እግዚአብሔርም ፡ ለአብርሃም ፡ የሰጣትን ፡ ምድር ፡ ትወርስ ፡ ዘንድ ፡ የአብርሃምን ፡ በረከት ፡ ለአንተ ፡ ይስጥህ ፥ ለዘርህም ፡ እንዲሁ ፡ ፭ እንደ ፡ አንተ ። ይስሐቅም ፡ ያዕቆብን ፡ ሰደደው ፥ እርሱም ፡ የያዕቆብና ፡ የዔሳው ፡ እናት ፡ የርብቃ ፡ ወንድም ፡ የሚሆን ፡ የሶርያዊ ፡ በቱኤል ፡ ልጅ ፡ ላባ ፡ ወዳለበት ፡ ወደ ፡ ሁለቱ ፡ ወንዞች ፡ መካከል ፡ ሄደ ።

፮ ዔሳውም ፡ ይስሐቅ ፡ ያዕቆብን ፡ እንደ ፡ ባረከው ፡ በየ ፡ ጊዜ ፥ ከዚያም ፡ ሚስትን ፡ ያገባ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ሁለት ፡ ወንዞች ፡ መካከል ፡ እንደ ፡ ሰደደው ፥ በባረከውም ፡ ጊዜ ፡— ከከነዓን ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ሚስትን ፡ አታግባ ፡ ብሎ ፡ እን ፯ ዳዘዘው ፥ ያዕቆብም ፡ የአባቱንና ፡ የእናቱን ፡ ቃል ፡ ሰምቶ ፡ ወደ ፡ ሁለቱ ፡ ወንዞች ፡ መካከል ፡ ፰ እንደ ፡ ሄደ ፥ የከነዓናውያንም ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ በአባቱ ፡ በይስሐቅ ፡ ፊት ፡ የተጠሉ ፡ እንደ ፡ ፱ ሆኑ ፡ ዔሳው ፡ በየ ፡ ጊዜ ፥ ዔሳው ፡ ወደ ፡ እስማኤል ፡ ሄደ ፥ ማዕሌትንም ፡ በፊት ፡ ካሉት ፡ ሚስቶቹ ፡ ጋር ፡ ሚስት ፡ ትሆነው ፡ ዘንድ ፡ አገባ ፤ እርስዋም ፡ የአብርሃም ፡ ልጅ ፡ የሆነ ፡ የእስማኤል ፡ ልጅና ፡ የነባዮት ፡ እኅት ፡ ናት ።

፲ ያዕቆብም ፡ ከቤርሳቤህ ፡ ወጥቶ ፡ ወደ ፡ ካራን ፡ ፲፩ ሄደ ። ወደ ፡ አንድ ፡ ስፍራም ፡ ደረሰ ፥ ፀሐይም ፡ ጠልቃ ፡ ነበርና ፡ ከዚያ ፡ አደረ ፤ በዚያም ፡ ስፍራ ፡ ድንጋይ ፡ አንሣ ፥ ከራሱም ፡ ፲፪ በታች ፡ ተንተርሶ ፡ በዚያ ፡ ስፍራ ፡ ተኛ ። ሕልምም ፡ አለመ ፤ እነሆም ፡ መሰላል ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ተተክሎ ፥ ራሱም ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ደርሶ ፥ እነሆም ፡ የእግዚአብሔር ፡ መላእክት ፡ ይወጡ ፲፫ በት ፡ ይወርዱበት ፡ ነበር ። እነሆም ፥ እግዚአብሔር ፡ በላዩ ፡ ቆሞበት ፡ ነበር ፥ እንዲህም ፡ አለ ፡— የአባትህ ፡ የአብርሃም ፡ አምላክ ፡ የይስሐቅም ፡ አምላክ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ፤ ይህችን ፡ አንተ ፡ የተኛህባትን ፡ ምድር ፡ ለአን ፲፬ ተም ፡ ለዘርህም ፡ እሰጣለሁ ፤ ዘርህም ፡ እንደ ፡ ምድር ፡ አሸዋ ፡ ይሆናል ፤ እስከ ፡ ምዕራብና ፡ እስከ ፡ ምሥራቅ ፡ እስከ ፡ ሰሜንና ፡ እስከ ፡ ደቡብ ፡ ትስፋፋለህ ፤ የምድርም ፡ አሕዛብ ፡ ፲፭ ሁሉ ፡ በአንተ ፡ በዘርህም ፡ ይባረካሉ ። እነሆም ፡ እኔ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነኝ ፥ በምትሄድበትም ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ እጠብቅሃለሁ ፥ ወደዚችም ፡ ምድር ፡ እመልስሃለሁ ፤ የነገርሁህን ፡ ሁሉ ፡ እስካደርግልህ ፡ ድረስ ፡ አልተውህምና ።

፲፮ ያዕቆብም ፡ ከእንቅልፉ ፡ ተነሥቶ ፡— በእውነት ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡ ስፍራ ፡ ነው ፤ እኔ ፡ ፲፯ አላወቅሁም ፡ ነበር ፡ አለ ። ፈራ ፥ እንዲህም ፡ አለ ፡— ይህ ፡ ስፍራ ፡ እንዴት ፡ ያስፈራ ፤ ይህ ፡ ስፍራ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ አይደለም ፤ ይህም ፡ የሰማይ ፡ ደጅ ፡ ነው ።

፲፰ ያዕቆብም ፡ ማልዶ ፡ ተነሣ ፥ ተንተርሶት ፡ የነበረውንም ፡ ድንጋይ ፡ ወስዶ ፡ ሐውልት ፡ አድርጎ ፡ አቆመው ፥ በላዩም ፡ ዘይትን ፡ አፈሰሰ ፲፱ በት ። ያዕቆብም ፡ ያንን ፡ ስፍራ ፡ ቤቴል ፡ ብሎ ፡ ጠራው ፤ አስቀድሞ ፡ ግን ፡ የዚያች ፡ ከተማ ፡ ፳ ስም ፡ ሎዛ ፡ ነበረ ። ያዕቆብም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ስእለት ፡ ተሳለ ፡— እግዚአብሔር ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ቢሆን ፥ በምሄድበትም ፡ በዚች ፡ መንገድ ፡ ቢጠብቀኝ ፥ የምበላውንም ፡ እንጀራ ፡ የምለብሰ ፳፩ ውንም ፡ ልብስ ፡ ቢሰጠኝ ፥ ወደ ፡ አባቴ ፡ ቤትም ፡ በጤና ፡ ብመለስ ፥ እግዚአብሔር ፡ ፳፪ አምላኬ ፡ ይሆንልኛል ፤ ለሐውልት ፡ የተከልሁት ፡ ይህም ፡ ድንጋይ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ይሆናል ፤ ከሰጠኸኝም ፡ ሁሉ ፡ ለአንተ ፡ ከአሥር ፡ አንዱን ፡ እሰጥሃለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

፩ ያዕቆብም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ሰዎች ፡ ፪ አገር ፡ ሄደ ። በሜዳውም ፡ እነሆ ፡ ጕድጓድን ፡ አየ ፥ በዚያም ፡ ሦስት ፡ የበጎች ፡ መንጎች ፡ በላዩ ፡ ተመስገው ፡ ነበር ፤ ከዚያ ፡ ጕድጓድ ፡ በጎቹን ፡ ያጠጡ ፡ ነበርና ፤ በጕድጓዱም ፡ አፍ ፡ ፫ የነበረው ፡ ድንጋይ ፡ ትልቅ ፡ ነበረ ። መንጎችም ፡ ሁሉ ፡ ከዚያ ፡ በተከማቹ ፡ ጊዜ ፡ ድንጋዩን ፡ ከጕድጓዱ ፡ አፍ ፡ ገለል ፡ አድርገው ፡ በጎቹን ፡ ያጠጡ ፡ ነበር ፤ ድንጋዩንም ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ መልሰው ፡ በጕድጓዱ ፡ አፍ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ይገጥሙት ፡ ነበር ።

፬ ያዕቆብም ፡— ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፥ እናንተ ፡ የወዴት ፡ ናችሁ ? አላቸው ። እነርሱም ፡— እኛ ፡ ፭ የካራን ፡ ነን ፡ አሉት ። የናኮርን ፡ ልጅ ፡ ላባን ፡ ታውቁታላችሁን ? አላቸው ። እነርሱም ፡— እናውቀዋለን ፡ አሉት ። እርሱ ፡— ደኅና ፡ ነውን ? ፮ አላቸው ። እነርሱም ፡— አዎን ፡ ደኅና ፡ ነው ፤

አሁንም ፡ ልጁ ፡ ራሔል ፡ ከበጎች ፡ ጋር ፡ መጣች ፡
፯ አሉት ። እርሱም ፡— ቀኑ ፡ ገና ፡ ቀትር ፡ ነው ፡÷
ከብቶቹ ፡ የሚከማቹበት ፡ ሰዓቱም ፡ ገና ፡ አል
ደረሰም ፤ አሁንም ፡ በጎቹን ፡ አጠጡና ፡ ሂዳ
፰ ችሁ ፡ አሰማሩአቸው ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡
አሉ ፡— መንጎች ፡ ሁሉ ፡ እስኪከማቹና ፡ ድንጋ
ዩን ፡ ከጕድጓዱ ፡ አፍ ፡ እስኪገለብጡት ፡ ድረስ ፡
አንችልም ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ በጎቹን ፡ እናጠ
፱ ጣለን ። እርሱም ፡ ገና ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ሲነጋ
ገር ፡ እነሆ ፡ የላባ ፡ ልጅ ፡ ራሔል ፡ ከአባትዋ ፡
በጎች ፡ ጋር ፡ ደረሰች ፤ እርስዋ ፡ የአባትዋን ፡
፲ በጎች ፡ ትጠብቅ ፡ ነበርና ። ያዕቆብም ፡ የእና
ቱን ፡ ወንድም ፡ የላባን ፡ ልጅ ፡ ራሔልንና ፡
የእኅቱን ፡ የላባን ፡ በጎች ፡ በየ ፡ ጊዜ ÷ ቀረበ ፡
ከጕድጓዱም ፡ አፍ ፡ ድንጋዩን ፡ ገለበጠ ÷ የእኅ
፲፩ ቱን ፡ የላባን ፡ በጎችንም ፡ አጠጣ ። ያዕቆብም ፡
ራሔልን ፡ ሳማት ÷ ቃሉንም ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡
፲፪ አለቀሰ ። ያዕቆብም ፡ የአባትዋ ፡ ዘመድና ፡ የር
ብቃ ፡ ልጅ ፡ መሆኑን ፡ ለራሔል ፡ አስታወቃት ፤
እርስዋም ፡ ሮጣ ፡ ሂዳ ፡ ለአባትዋ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡
ነገረችው ።

፲፫ ላባም ፡ የእኅቱን ፡ ልጅ ፡ የያዕቆብን ፡ ወሬ ፡
በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ሊቀበለው ፡ ሮጠ ÷ አቅፎም ፡
ሳመው ÷ ወደ ፡ ቤቱም ፡ አገባው ። ነገሩንም ፡
፲፬ ሁሉ ፡ ለላባ ፡ ነገረው ። ላባም ፡— በእውነት ፡
አንተ ፡ አጥንቴ ፡ ሥጋዬም ፡ ነህ ፡ አለው ። አንድ ፡
ወር ፡ የሚያህልም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተቀመጠ ።
፲፭ ላባም ፡ ያዕቆብን ፡— ወንድሜ ፡ ስለ ፡ ሆንህ ፡ በከ
ንቱ ፡ ታገለግለኛለህን? ምንዳህ ፡ ምንድር ፡ ነው?
፲፮ ንገረኝ ፡ አለው ። ለላባም ፡ ሁለት ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡
ነበሩት ፤ የታላቂቱ ፡ ስም ፡ ልያ ፡ የታናሺቱ ፡
፲፯ ስም ፡ ራሔል ፡ ነበረ ። ልያም ፡ ዓይነ ፡ ልም ፡
ነበረች ፤ ራሔል ፡ ግን ፡ መልከ ፡ መልካም ፡ ነበ
፲፰ ረች ፡ ፊትዋም ፡ ውብ ፡ ነበረ ። ያዕቆብም ፡ ራሔ
ልን ፡ ወደደ ፤ እንዲህም ፡ አለ ፡— ስለ ፡ ታናሺቱ ፡
ልጅህ ፡ ስለ ፡ ራሔል ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ እገዛል
፲፱ ሃለሁ ። ላባም ፡— ለሌላ ፡ ሰው ፡ ከምሰጣት ፡
ይልቅ ፡ ለአንተ ፡ ብሰጣት ፡ ይሻላል ፤ ከእኔ ፡
፳ ጋር ፡ ተቀመጥ ፡ አለ ። ያዕቆብም ፡ ስለ ፡ ራሔል ፡
ሰባት ፡ ዓመት ፡ ተገዛ ፤ እርስዋንም ፡ ይወድዳት ፡
ስለ ፡ ነበረ ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ጥቂት ፡
ቀን ፡ ሆነለት ።

፳፩ ያዕቆብም ፡ ላባን ፡— ወደ ፡ እርስዋ ፡ እገባ ፡
ዘንድ ፡ ሚስቴን ፡ ስጠኝ ÷ ቀኔ ፡ ተፈጽሞአልና ፡
፳፪ አለው ። ላባም ፡ የዚያን ፡ ስፍራ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
፳፫ ሰበሰበ ÷ ሰርግም ፡ አደረገ ። በመሸም ፡ ጊዜ ፡
ልጁን ፡ ልያን ፡ ወስዶ ፡ ለያዕቆብ ፡ አገባለት ፤
፳፬ ያዕቆብም ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ገባ ። ላባም ፡ ለልጁ ፡
ለልያ ፡ ባሪያይቱን ፡ ዘለፋን ፡ ባሪያ ፡ ትሆናት ፡
፳፭ ዘንድ ፡ ሰጣት ። በነጋም ፡ ጊዜ ፡ እነሆ ፡ ልያ ፡
ሆና ፡ ተገኘች ፤ ላባንም ፡— ምነው ፡ እንደዚህ ፡
አደረግህብኝ ? ያገለገልሁህ ፡ ስለ ፡ ራሔል ፡
አልነበረምን? ለምን ፡ አታለልኸኝ? አለው ።
፳፮ ላባም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— በአገራችን ፡ ታላቂቱ ፡
ሳለች ÷ ታናሺቱን ፡ እንሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ወግ ፡ አይ
ደለም ፤ ይህችንም ፡ ሳምንት ፡ ፈጽም ፤ ሌላ ፡ ፳፯
ሰባት ፡ ዓመት ፡ ደግሞ ፡ እኔን ፡ ስለምታገለግ
ለኝ ፡ አገልግሎት ፡ እርስዋን ፡ ደግሞ ፡ እሰጥሃ
ለሁ ። ያዕቆብም ፡ እንዲህ ፡ አደረገ ÷ ይህች ፳፰
ንም ፡ ሳምንት ፡ ፈጸመ ፤ ልጁን ፡ ራሔልንም ፡
ለእርሱ ፡ ሚስት ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ሰጠው ።
ላባም ፡ ለልጁ ፡ ለራሔል ፡ ባሪያይቱን ፡ ባላን ፡ ፳፱
ባሪያ ፡ ትሆናት ፡ ዘንድ ፡ ሰጣት ። ያዕቆብም ፡ ፴
ወደ ፡ ራሔል ፡ ደግሞ ፡ ገባ ። ራሔልንም ፡
ከልያ ፡ ይልቅ ፡ ወደዳት ፤ ሌላ ፡ ሰባት ፡ ዓመ
ትም ፡ ተገዛለት ።

እግዚአብሔርም ፡ ልያ ፡ የተጠላች ፡ መሆን ፴፩
ዋን ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ማኅፀንዋን ፡ ከፈተላት ፤ ራሔል ፡
ግን ፡ መካን ፡ ነበረች ። ልያም ፡ ፀነሰች ÷ ወንድ ፡ ፴፪
ልጅንም ፡ ወለደች ÷ ስሙንም ፡ ሮቤል ፡ ብላ ፡
ጠራችው ፤ እግዚአብሔር ፡ መከራዬን ፡ አይቶ
አልና ÷ እንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ ባሌ ፡ ይወድደኛል ፡
ብላለችና ። ደግሞም ፡ ፀነሰች ÷ ወንድ ፡ ልጅ ፴፫
ንም ፡ ወለደች ፤ እኔ ፡ እንደ ፡ ተጠላሁ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ስለ ፡ ሰማ ፡ ይህን ፡ ደገመኝ ፡ አለች ፤
ስሙንም ፡ ስምዖን ፡ ብላ ፡ ጠራችው ። ደግሞም ፡ ፴፬
ፀነሰች ÷ ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ወለደች ፤ አሁ
ንም ፡ ባሌ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይጠጋል ÷ ሦስት ፡ ወን
ዶች ፡ ልጆችን ፡ ወልጀለታለሁና ፡ አለች ፤ ስለ
ዚህም ፡ ስሙን ፡ ሌዊ ፡ ብላ ፡ ጠራችው ። ደግ ፴፭
ሞም ፡ ፀነሰች ÷ ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ወለደች ፤
በዚህም ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግና
ለሁ ፡ አለች ፤ ስለዚህም ፡ ስሙን ፡ ይሁዳ ፡ ብላ ፡
ጠራችው ። መውለድንም ፡ አቆመች ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

ራሔልም ፡ ለያዕቆብ ፡ ልጆችን ፡ እንዳልወለ ፩
ደች ፡ በየች ፡ ጊዜ ፡ በእኅትዋ ፡ ቀናችባት ፤ ያዕ
ቆብንም ፡— ልጅ ፡ ስጠኝ ፤ ይህስ ፡ ካልሆነ ፡ እሞ
ታለሁ ፡ አለችው ። ያዕቆብም ፡ ራሔልን ፡ ተቈ ፪
ጥቶ ፡— በውኑ ፡ እኔ ፡ የሆድን ፡ ፍሬ ፡ በነሣሽ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ቦታ ፡ ነኝን ? አላት ። እርስ ፫
ዋም ፡— ባሪያዬ ፡ ባላ ፡ እነሆ ፡ አለች ፤ ድረስባት ፤
በእኔም ፡ ጭን ፡ ላይ ፡ ትውለድ ÷ የእርስዋም ፡
ልጆች ፡ ለእኔ ፡ ደግሞ ፡ ይሁኑልኝ ፡ አለች ።
ባሪያዋን ፡ ባላንም ፡ ሚስት ፡ ትሆነው ፡ ዘንድ ፡ ፬
ለእርሱ ፡ ሰጠችው ፤ ያዕቆብም ፡ ደረሰባት ።
ባላም ፡ ፀነሰች ÷ ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ለያዕቆብ ፡ ፭
ወለደችለት ። ራሔልም ፡— እግዚአብሔር ፡ ፮
ፈረደልኝ ÷ ቃሌንም ፡ ደግሞ ፡ ሰማ ÷ ወንድ ፡
ልጅንም ፡ ሰጠኝ ፡ አለች ፤ ስለዚህ ፡ ስሙን ፡
ዳን ፡ ብላ ፡ ጠራችው ። የራሔልም ፡ ባሪያ ፡ ባላ ፡ ፯
ደግማ ፡ ፀነሰች ÷ ለያዕቆብም ፡ ሁለተኛ ፡ ወንድ ፡
ልጅን ፡ ወለደች ። ራሔልም ፡— ብርቱ ፡ ትግ ፰
ልን ፡ ከእኅቴ ፡ ጋር ፡ ታገልሁ ÷ አሸነፍሁም ፡
አለች ፤ ስሙንም ፡ ንፍታሌም ፡ ብላ ፡ ጠራችው ።
ልያም ፡ መውለድን ፡ እንዳቆመች ፡ ባየች ፡ ፱
ጊዜ ፡ ባሪያዋን ፡ ዘለፋን ፡ ወሰደች ÷ ሚስት ፡ ትሆን

፲ ውም ፡ ዘንድ ፡ ለያዕቆብ ፡ ሰጠችው ። የልያ ፡
ባሪያ ፡ ዘለፋም ፡ ወንድ ፡ ልጅን ፡ ለያዕቆብ ፡ ወለ
፲፩ ደች ። ልያም ፡— ጉድ ፡ አለች ፤ ስሙንም ፡ ጋድ ፡
፲፪ ብላ ፡ ጠራችው ። የልያ ፡ ባሪያ ፡ ዘለፋም ፡ ዳግ
መኛ ፡ ለያዕቆብ ፡ ወንድ ፡ ልጅን ፡ ወለደች ።
፲፫ ልያም ፡— ደስታ ፡ ሆነልኝ ፤ ሴቶች ፡ ያመሰግኑኛ
ልና ፡ አለች ፤ ስሙንም ፡ አሴር ፡ ብላ ፡ ጠራ
ችው ።

፲፬ ሮቤል ፡ ስንዴ ፡ በሚታጨድበት ፡ ወራት ፡
ወጣ ÷ በእርሻም ፡ እንኮይ ፡ አገኘ ÷ ለእናቱ ፡
ለልያም ፡ አመጣላት ። ራሔልም ፡ ልያን ፡—
፲፭ የልጅሽን ፡ እንኮይ ፡ ስጪኝ ፡ አለቻት ። እርስ
ዋም ፡— ባሌን ፡ መውሰድሽ ፡ በውኑ ፡ ጥቂት ፡
ነገር ፡ ነውን ? አሁን ፡ ደግሞ ፡ የልጄን ፡ እንኮይ ፡
ልትወስጂ ፡ ትፈልጊያለሽን ? አለቻት ። ራሔ
ልም ፡— እንኪያስ ፡ ስለ ፡ ልጅሽ ፡ እንኮይ ፡ በዚ
ህች ፡ ሌሊት ፡ ከአንቺ ፡ ጋር ፡ ይተኛ ፡ አለች ።
፲፮ ያዕቆብም ፡ ሲመሽ ፡ ከዱር ፡ ገባ ÷ ልያም ፡ ልት
ቀበለው ፡ ወጣች ፡ እንዲህም ፡ አለችው ፡— ወደ ፡
እኔ ፡ ትገባለህ ፤ በልጄ ፡ እንኮይ ፡ በእርግጥ ፡
ተከራይቼሃለሁና ። በዚያችም ፡ ሌሊት ፡ ከእ
፲፯ ርስዋ ፡ ጋር ፡ ተኛ ። እግዚአብሔርም ፡ የል
ያን ፡ ጸሎት ፡ ሰማ ÷ ፀነሰችም ÷ አምስተኛ ፡
፲፰ ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ለያዕቆብ ፡ ወለደች ። ልያም ፡—
ባሪያዬን ፡ ለባሌ ፡ ስለ ፡ ሰጠሁ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዋጋዬን ፡ ሰጠኝ ፡ አለች ፤ ስሙንም ፡ ይሳኮር ፡
፲፱ ብላ ፡ ጠራችው ። ልያም ፡ ደግማ ፡ ፀነሰች ÷
ስድስተኛ ፡ ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ለያዕቆብ ፡ ወለ
፳ ደች ። ልያም ፡— እግዚአብሔር ፡ መልካም ፡
ስጦታን ፡ ሰጠኝ ፤ እንግዲህስ ፡ ባሌ ፡ ከእኔ ፡
ጋር ፡ ይኖራል ÷ ስድስት ፡ ልጆችን ፡ ወልጄለ
ታለሁና ፡ አለች ፤ ስሙንም ፡ ዛብሎን ፡ ብላ ፡
፳፩ ጠራችው ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ሴት ፡ ልጅን ፡
፳፪ ወለደች ÷ ስምዋንም ፡ ዲና ፡ አለቻት ። እግ
ዚአብሔርም ፡ ራሔልን ፡ አሰበ ÷ እግዚአብሔ
ርም ፡ ተለመናት ÷ ማኅፀንዋንም ፡ ከፈተላት ፤
፳፫ ፀነሰችም ÷ ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ወለደችና ፡—
እግዚአብሔር ፡ ስድቤን ፡ አስወገደ ፡ አለች ፤
፳፬ ስሙንም ፡— እግዚአብሔር ፡ ሁለተኛ ፡ ወንድ ፡
ልጅን ፡ ይጨምርልኝ ፡ ስትል ፡ ዮሴፍ ፡ ብላ ፡
ጠራችው ።

፳፭ ራሔልም ፡ ዮሴፍን ፡ ከወለደች ፡ በኋላ ፡ ያዕ
ቆብ ፡ ላባን ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— ወደ ፡ ስፍራዬ ፡
ወደ ፡ አገሬም ፡ እመለስ ፡ ዘንድ ፡ አሰናብተኝ ።
፳፮ ስለ ፡ እነርሱ ፡ የተገዛሁላቸውን ፡ ሚስቶቼንና ፡
ልጆቼን ፡ ስጠኝና ፡ ልሂድ ፤ የተገዛሁልህን ፡
፳፯ መገዛት ፡ ታውቃለህና ። ላባም ፡— በዓይንህ ፡
ፊት ፡ ሞገስን ፡ የማገኝ ፡ ብሆንስ ፡ ከዚሁ ፡ ተቀ
መጥ ፤ እግዚአብሔር ፡ በአንተ ፡ ምክንያት ፡
እንደ ፡ ባረከኝ ፡ ተመልክቼአለሁና ፡ አለው ።
፳፰ ደመወዝህን ፡ ንገረኝ ÷ እርሱንም ፡ እሰጥሃለሁ ፡
፳፱ አለ ። እርሱም ፡ አለው ፡— እንዴት ፡ እንዳገ
ለገልሁህ ÷ ከብትህንም ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ጠበ
፴ ቅሁልህ ፡ አንተ ፡ ታውቃለህ ። ከእኔ ፡ መምጣት ፡
በፊት ፡ የነበረህ ፡ ጥቂት ፡ ነበርና ÷ ዛሬም ፡
እጅግ ፡ በዛ ፤ ወደ ፡ አንተ ፡ በመምጣቴም ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ባረከህ ፤ አሁንም ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡
፴፩ ለቤቴ ፡ የምሠራው ፡ መቼ ፡ ነው ? እርሱም ፡—
የምሰጥህ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለ ። ያዕቆብም ፡
አለው ፡— ምንም ፡ አትሰጠኝ ፤ ይህንም ፡ ነገር ፡
ብታደርግልኝ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ በጎችህን ፡ አበላ
፴፪ ለሁ ፡ እጠብቃለሁም ። ዛሬ ፡ በመንጎችህ ፡
በኩል ፡ አልፋለሁ ÷ በዚያም ፡ ከበጎችህ ፡ መካ
ከል ፡ ዝንጕርጕርና ፡ ነቍጣ ፡ ያለበቱን ፡ ጥቁሩ
ንም ፡ በግ ፡ ሁሉ ÷ ከፍየሎቹም ፡ ነቍጣና ፡ ዝን
ጕርጕር ፡ ያለበቱን ፡ እለያለሁ ፤ እነርሱም ፡ ደመ
፴፫ ወዜ ፡ ይሆናሉ ። ስለዚህም ፡ በፊትህ ፡ ያለ
ውን ፡ ደመወዜን ፡ ለመመልከት ፡ በመጣህ ፡
ጊዜ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ጻድቅነቴ ፡ ይመሰክርልኛል ፤
ከፍየሎች ፡ ዝንጕርጕርና ፡ ነቍጣ ፡ የሌለበት ፡
ከበግ ፡ ጠቦቶችም ፡ ጥቁር ፡ ያልሆኑ ፡ ሁሉ ÷
እርሱ ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ቢገኝ ፡ እንደ ፡ ተሰረቀ ፡
፴፬ ይቈጠርብኝ ። ላባም ፡— እነሆ ፡ እንደ ፡ ቃልህ ፡
፴፭ ይሁን ፡ አለ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ከተባዕቶቹ ፡ ፍየ
ሎች ፡ ሽመልመሌ ፡ መሳይና ፡ ነቍጣ ፡ ያለባቸ
ውን ÷ ከእንስቶቹም ፡ ፍየሎች ፡ ዝንጕርጕርና ፡
ነቍጣ ፡ ያለባቸውን ÷ ነጭ ፡ ያለበትን ፡ ማንኛ
ውንም ፡ ሁሉ ÷ ከበጎቹም ፡ መካከል ፡ ጥቁሩን ፡
፴፮ በግ ፡ ሁሉ ፡ ለይቶ ፡ ለልጆቹ ፡ ሰጣቸው ። በእ
ርሱና ፡ በያዕቆብ ፡ መካከልም ፡ የሦስት ፡ ቀን ፡
መንገድ ፡ ያህል ፡ አራቃቸው ፤ ያዕቆብም ፡ የቀ
ሩትን ፡ የላባን ፡ በጎች ፡ ይጠብቅ ፡ ነበር ።
፴፯ ያዕቆብም ፡ ልብን ፡ ለውዝ ፡ ኤርሞን ፡ ከሚ
ባሉ ፡ እንጨቶች ፡ እርጥብ ፡ በትርን ፡ ወስዶ ፡
በበትሮቹ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፡ ነጭ ፡ እንዲታይ ፡
፴፰ ነጭ ፡ ሽመልመሌ ፡ አድርጎ ፡ ላጣቸው ። የላ
ጣቸውንም ፡ በትሮች ፡ በጎቹ ፡ ውኃ ፡ ሊጠጡ ፡
በመጡ ፡ ጊዜ ፡ በውኃ ፡ ማጠጫው ፡ ገንዳ ፡
ውስጥ ፡ በበጎቹ ፡ ፊት ፡ አኖራቸው ፤ በጎቹ ፡
ውኃ ፡ ሊጠጡ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ይጐመጁ ፡
፴፱ ነበር ። በጎቹም ፡ በትሮቹን ፡ አይተው ፡ ከመ
ጐምጀታቸው ፡ የተነሣ ፡ ፀነሱ ፤ በጎቹም ፡ ሽመ
ልመሌ ፡ መሳይና ፡ ዝንጕርጕር ፡ ነቍጣም ፡ ያለ
፵ በቱን ፡ ወለዱ ። ያዕቆብም ፡ ጠቦቶቹን ፡ ለየ ÷
ሽመልመሌ ፡ መሳይና ፡ ጥቁር ፡ ያለባቸውን ፡
በጎቹንም ፡ ሁሉ ፡ በላባ ፡ በጎች ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡
አኖረ ፤ መንጎቹንም ፡ ለብቻቸው ፡ አቆማቸው ÷
ወደ ፡ ላባም ፡ በጎች ፡ አልጨመራቸውም ።
፵፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ የበረቱት ፡ በጎች ፡ በጐመጁ ፡
ጊዜ ÷ በጎቹ ፡ በትሮቹን ፡ አይተው ፡ በበትሮቹ ፡
አምሳል ፡ ይፀንሱ ፡ ዘንድ ፡ ያዕቆብ ፡ በትሮቹን ፡
በውኃ ፡ ማጠጫው ፡ ገንዳ ፡ ውስጥ ፡ ከበጎቹ ፡
፵፪ ፊት ፡ አደረገ ፤ በደከሙ ፡ በጎችም ፡ ፊት ፡ በት
ሩን ፡ አያደርገውም ፡ ነበር ፤ የደከሙትም ፡
፵፫ ለላባ ÷ የበረቱትም ፡ ለያዕቆብ ፡ ሆኑ ። ያ ፡ ሰውም ፡
እጅግ ፡ ባለ ፡ ጠጋ ፡ ሆነ ፤ ብዙም ፡ ከብት ፡ ሴቶ
ችም ፡ ወንዶችም ፡ ባሪያዎች ፡ ግመሎችም ፡ አህ
ዮችም ፡ ሆኑለት ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፩ ።

፩ ያዕቆብም ፡ የላባ ፡ ልጆች ፡ ያሉትን ፡ ነገር ፡— ያዕቆብ ፡ ለአባታችን ፡ የሆነውን ፡ ሁሉ ፡ ወሰደ ፤ ይህንም ፡ ሁሉ ፡ ክብር ፡ ከአባታችን ፡ ከብት ፡ አገኘ ፡ ሲሉ ፡ ሰማ ። ፪ ያዕቆብም ፡ የላባን ፡ ፊት ፡ አየ ፥ እነሆም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ዱሮው ፡ አልሆነም ። ፫ እግዚአብሔርም ፡ ያዕቆብን ፡— ወደ ፡ አባትህ ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ ዘመዶችህም ፡ ተመለስ ፤ ከአንተም ፡ ጋር ፡ እሆናለሁ ፡ አለው ። ፬ ያዕቆብም ፡ ልኮ ፡ ራሔልንና ፡ ልያን ፡ ወደ ፡ በጎቹ ፡ ስፍራ ፡ ወደ ፡ሜዳ ፡ ጠራቸው ፥ ፭ እንዲህም ፡ አላቸው ፡—የአባታችሁ ፡ ፊት ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ዱሮ ፡ እንዳልሆነ ፡ አያለሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የአባቴ ፡ አምላክ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ነው ። ፮ እኔ ፡ ባለኝ ፡ ጕልበቴ ፡ ሁሉ ፡ አባታችሁን ፡ እንዳገለገልሁ ፡ ታውቃላችሁ ። ፯ አባታችሁ ፡ ግን ፡ አታለለኝ ፥ ደመወዜንም ፡ አሥር ፡ ጊዜ ፡ ለወጠ ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ክፉን ፡ ያደርግብኝ ፡ ዘንድ ፡ አልፈቀደለትም ። ፰ ደመወዝህ ፡ ዝንጕርጕሮች ፡ ይሁኑ ፡ ቢለኝ ፡ በጎቹ ፡ ሁሉ ፡ ዝንጕርጕሮችን ፡ ወለዱ ፤ ሽመልመሌ ፡ መሰየቹ ፡ ደመወዝህ ፡ ይሁኑ ፡ ቢለኝ ፡ በጎቹ ፡ ሁሉ ፡ ሽመልመሌ ፡ መሰ የችን ፡ ወለዱ ። ፱ እግዚአብሔርም ፡ የአባታችሁን ፡ በጎች ፡ ሁሉ ፡ ነሥቶ ፡ ለእኔ ፡ ሰጠኝ ። ፲ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በጎቹ ፡ በጐመጁ ፡ ጊዜ ፡ ዓይኔን ፡ አንሥቼ ፡ በሕልም ፡ አየሁ ፤ እነሆም ፥ በበጎችና ፡ በፍየሎች ፡ ላይ ፡ የሚንጠላጠሉት ፡ የበጎችና ፡ የፍየሎች ፡ አውራዎች ፡ ሽመልመሌ ፡ መሰየችና ፡ ዝንጕርጕሮች ፡ ነቍጣ ፡ ያለባቸውም ፡ ነበሩ ። ፲፩ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ በሕልም ፡— ያዕቆብ ፡ ሆይ ፡ አለኝ ፤ እኔም ፡—እነሆኝ ፡ አልሁት ። ፲፪ እንዲህም ፡ አለኝ ፡—ዓይንህን ፡ አቅንተህ ፡ እይ ፤ በበጎችና ፡ በፍየሎች ፡ ላይ ፡ የሚንጠላጠሉት ፡ የበጎችና ፡ የፍየሎች ፡ አውራዎች ፡ ሽመልመሌ ፡ መሰየችና ፡ ዝንጕርጕሮች ፡ ነቍጣ ፡ ያለባቸውም ፡ ናቸው ፤ ላባ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ የሚ ያደርገውን ፡ ሁሉ ፡ አይቼአለሁና ። ፲፫ ሐውልት ፡ የቀባህበት ፡ በዚያም ፡ ለእኔ ፡ ስእለት ፡ የተሳልህበት ፡ የቤቴል ፡ አምላክ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ አሁንም ፡ ተነሥተህ ፡ ከዚህ ፡ አገር ፡ ውጣ ፥ ወደ ፡ ተወለድህበትም ፡ ምድር ፡ ተመለስ ። ፲፬ ራሔልና ፡ ልያም ፡ መልሰው ፡ እንዲህ ፡ አሉት ፡—በአባታችን ፡ ቤት ፡ ለእኛ ፡ ድርሻና ፡ ርስት ፡ በውኑ ፡ ቀርቶልናልን ? ፲፭ እኛ ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ባዕድ ፡ የተቈጠርን ፡ አይደለንምን ? እርሱ ፡ እኛን ፡ ሸጦ ፡ ዋጋችንን ፡ በልቶአልና ። ፲፮ ስለዚህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአባታችን ፡ የነሣው ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ሀብት ፡ ለእኛና ፡ ለልጆቻችን ፡ ነው ፤ አሁንም ፡ እግዚአብሔር ፡ ያለህን ፡ ሁሉ ፡ አድርግ ።

፲፯ ያዕቆብም ፡ ተነሣ ፥ ልጆቹንና ፡ ሚስቶቹንም ፡ ፲፰ በግመሎች ፡ ላይ ፡ አስቀመጠ ፤ መንጎቹንም ፡ ሁሉ ፥ የቤቱንም ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፥ በሁለት ፡ ወንዞች ፡ መካከል ፡ ሳለ ፡ ያገኛቸውን ፡ ከብቶች ፡ ሁሉ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ አባቱ ፡ ወደ ፡ ይስሐቅ ፡ ወደ ፡ ከነዓን ፡ ምድር ፡ ሄደ ። ፲፱ ላባ ፡ ግን ፡ በጎቹን ፡ ለመሸለት ፡ ሄዶ ፡ ነበር ፤ ራሔልም ፡ የአባትዋን ፡ ተራፊም ፡ ሰረቀች ። ፳ ያዕቆብም ፡ የሶርያውን ፡ ሰው ፡ ላባን ፡ ከድቶ ፡ ኰበለለ ፥ መኰብለሉንም ፡ አልነገረውም ። ፳፩ እርሱም ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ይዞ ፡ ኰበለለ ፤ ተነሥቶም ፡ ወንዙን ፡ ተሻገረ ፥ ፊቱንም ፡ ወደ ፡ ገለዓድ ፡ ተራራ ፡ አቀና ።

፳፪ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ የያዕቆብ ፡ መኰብለል ፡ ለላባ ፡ ተነገረው ። ፳፫ ከወንድሞቹም ፡ ጋር ፡ ሆኖ ፡ የሰባት ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ ያህል ፡ ተከተለው ፥ በገለዓድ ፡ ተራራም ፡ ላይ ፡ ደረሰበት ። ፳፬ እግዚአብሔርም ፡ ወደ ፡ ሶርያው ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ላባ ፡ በሌሊት ፡ ሕልም ፡ መጥቶ ፡—ያዕቆብን ፡ በክፉ ፡ ነገር ፡ እንዳትናገረው ፡ ተጠንቀቅ ፡ አለው ። ፳፭ ላባም ፡ ደረሰበት ፤ ያዕቆብም ፡ ድንኳኑን ፡ በተራራው ፡ ተክሎ ፡ ነበር ፤ ላባም ፡ ከወንድሞቹ ፡ ጋር ፡ በገለዓድ ፡ ተራራ ፡ ድንኳኑን ፡ ተከለ ። ፳፮ ላባም ፡ ያዕቆብን ፡ አለው ፡—ለምን ፡ እንዲህ ፡ አደረግህ ? ከእኔ ፡ ከድተህ ፡ ኰበለልህ ፥ ልጆቼንም ፡ በሰይፍ ፡ እንደ ፡ ተማረኩ ፡ ዓይነት ፡ ነዳሃቸው ። ፳፯ ስለ ፡ ምን ፡ በስውር ፡ ሸሽህ ? ከእኔም ፡ ከድተህ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ኰበለልህ ? በደስታና ፡ በዘፈን ፡ በከበሮና ፡ በበገና ፡ እንድሰድድህ ፡ ለምን ፡ አልነገርኸኝም ? ፳፰ ወንዶቼንና ፡ ሴቶቹን ፡ ልጆቼን ፡ እንድስም ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አልፈቀድህልኝም ? ይህንም ፡ በስንፍና ፡ አደረግህ ። ፳፱ ክፉ ፡ አደርግባችሁ ፡ ዘንድ ፡ ኃይል ፡ ነበረኝ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የአባታችሁ ፡ አምላክ ፡ ትናንት ፡—ያዕቆብን ፡ በክፉ ፡ ነገር ፡ እንዳትናገረው ፡ ተጠንቀቅ ፡ ብሎ ፡ ነገረኝ ። ፴ አሁንም ፡ የአባትህን ፡ ቤት ፡ ከናፈቅህ ፡ ሂድ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አምላኬን ፡ ለምን ፡ ሰረቅህ ? ፴፩ ያዕቆብም ፡ መለሰ ፡ ላባንም ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡—ልጆችህን ፡ ከእኔ ፡ የምትቀማኝ ፡ ስለ ፡ መሰለኝና ፡ ስለ ፡ ፈራሁ ፡ ይህን ፡ አደረግሁ ። ፴፪ አምላክችህን ፡ የምታገኝበት ፡ሰው ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ ይሙት ፤ የአንተ ፡ የሆነውም ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ይገኝ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በወንድሞቻችን ፡ ፊት ፡ ፈልግ ፥ ለአንተም ፡ ውሰደው ፡ አለ ። ራሔል ፡ እንደ ፡ ሰረቀቻቸው ፡ ያዕቆብ ፡ አያውቅም ፡ ነበርና ።

፴፫ ላባም ፡ ወደ ፡ ያዕቆብ ፡ ድንኳንና ፡ ወደ ፡ ልያ ፡ ድንኳን ፡ ወደ ፡ ሁለቱም ፡ ባሪያዎች ፡ ድንኳን ፡ ገባ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አላገኘም ። ከልያም ፡ ድንኳን ፡ ወጥቶ ፡ ወደ ፡ ራሔል ፡ ድንኳን ፡ ገባ ። ፴፬ ራሔልም ፡ ተራፊምን ፡ ወስዳ ፡ ከግመል ፡ ኮርቻ ፡ በታች ፡ ሸሸገች ፥ በላዩም ፡ ተቀመጠችበት ። ላባም ፡ ድንኳኑን ፡ ሁሉ ፡ ፈለገ ፥ አንዳችም ፡ አላገኘም ። ፴፭ እርስዋም ፡ አባትዋን ፡— በፊትህ ፡ ለመቆም ፡ ስላልቻልሁ ፡ አትቈጣብኝ ፤ በሴቶች ፡ የሚደርስ ፡ ግዳጅ ፡ ደርሶብኛልና ፡ አለችው ። እርሱም ፡ ፈለገ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ተራፊምን ፡ አላገኘም ።

፴፮ ያዕቆብም ፡ ተቈጣ ፡ ላባንም ፡ ወቀሰው ፤

ያዕቆብም ፡ መለሰ ፡ ላባንም ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡—
የበደልሁህ ፡ በደል ፡ ምንድር ፡ ነው ? ኃጢአ
ቴስ ፡ ምንድር ፡ ነው ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ያሳደድ
፴፯ ኸኝ ? አሁንም ፡ ዕቃዬን ፡ ሁሉ ፡ በረበርህ ፤
ከቤትህስ ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ምን ፡ አገኘህ ? እነርሱ ፡
በእኛ ፡ በሁለታችን ፡ መካከል ፡ ይፈርዱ ፡ ዘንድ ፡
በወንድሞቼና ፡ በወንድሞችህ ፡ ፊት ፡ አቅር
፴፰ በው ። ሀያ ፡ ዓመት ፡ ሙሉ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነበ
ርሁ ፤ በጎችህና ፡ ፍየሎችህ ፡ አልጨነገፉም ፤
፴፱ የመንጎችህንም ፡ ጠቦቶች ፡ አልበላሁም ፤ አውሬ ፡
የሰበረውን ፡ አላመጣሁልህም ፡ ነበር ፤ እኔ ፡
ስለ ፡ እርሱ ፡ እከፍልህ ፡ ነበርሁ ፤ በቀንም ፡
በሌሊትም ፡ የተሰረቀውን ፡ ከእጄ ፡ ትሻው ፡
፵ ነበርህ ። የቀን ፡ ሐሩር ፡ የሌሊት ፡ ቍር ፡ ይበ
፵፩ ላኝ ፡ ነበር ÷ እንቅልፍም ፡ ከዓይኔ ፡ ጠፋ ። እን
ዲሁ ፡ በአንተ ፡ ቤት ፡ ሀያ ፡ ዓመት ፡ ነበርሁ ፤
አሥራ ፡ አራት ፡ ዓመት ፡ ስለ ፡ ሁለቱ ፡ ሴቶች ፡
ልጆችህ ÷ ስድስት ፡ ዓመትም ፡ ስለ ፡ በጎችህ ፡
ተገዛሁልህ ፤ ደመወዜንም ፡ አሥር ፡ ጊዜ ፡ ለዋ
፵፪ ወጥኸው ። የአባቴ ፡ የአብርሃም ፡ አምላክ ፡
የይስሐቅም ፡ ፍርሃት ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ባይሆንስ ፡
ዛሬ ፡ ባዶ ፡ እጄን ፡ በሰደድኸኝ ፡ ነበር ፤ እግዚ
አብሔር ፡ መከራዬንና ፡ የእጆቼን ፡ ድካም ፡ አየ ÷
ትናንትም ፡ ገሠጸህ ።

፵፫ ላባም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ለያዕቆብ ፡ መለሰ
ለት ፡— ሴቶቹ ፡ ልጆች ፡ ልጆቼ ፡ ናቸው ÷ ሕፃ
ናቱም ፡ ሕፃናቴ ፡ ናቸው ÷ መንጎቹም ፡ መን
ጎቼ ፡ ናቸው ÷ የምታየውም ፡ ሁሉ ፡ የእኔ ፡ ነው ፤
ዛሬም ፡ በእነዚህ ፡ በሴቶች ፡ ልጆቼና ፡ በወለዱ
አቸው ፡ ልጆቻቸው ፡ ላይ ፡ ምን ፡ ላደርግ ፡ ይቻ
፵፬ ላል ? አሁንም ፡ ና ÷ አንተና ፡ እኔ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
እንጋባ ፤ በእኔና ፡ በአንተ ፡ መካከልም ፡ ምስ
፵፭ ክር ፡ ይሁን ። ያዕቆብም ፡ ድንጋይ ፡ ወስዶ ፡
፵፮ ሐውልት ፡ አቆመ ። ያዕቆብም ፡ ወንድሞቹን ፡—
ድንጋይ ፡ ሰብስቡ ፡ አላቸው ፤ እነርሱም ፡ ድን
ጋይ ፡ ሰብስበው ፡ ከመሩ ፤ በድንጋዩም ፡ ክምር ፡
፵፯ ላይ ፡ በሉ ። ላባም ፡ ይጋርሠሀዱታ ፡ ብሎ ፡
፵፰ ጠራት ፤ ያዕቆብም ፡ ገለዓድ ፡ አላት ። ላባም ፡—
ይህች ፡ ክምር ፡ በእኔና ፡ በአንተ ፡ መካከል ፡
ዛሬ ፡ ምስክር ፡ ናት ፡ አለ ። ስለዚህም ፡ ስምዋ ፡
፵፱ ገለዓድ ፡ ተባለ ፤ ደግሞም ፡ ምጽጳ ፡ ተባለ ፡—
እኛ ፡ በተለያየን ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእ
ኔና ፡ በአንተ ፡ መካከል ፡ ሆኖ ፡ ይጠብቅ ፡ ብሎ
፶ አልና ። ልጆቼን ፡ ብትበድላቸው ፡ ወይም ፡
በላያቸው ፡ ሚስቶችን ፡ ብታገባባቸው ፡ ከእኛ ፡
ጋር ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ የለም ፤ እግዚአብሔር ፡ በእ
፶፩ ኔና ፡ በአንተ ፡ መካከል ፡ ምስክር ፡ ነው ። ላባም ፡
ያዕቆብን ፡ አለው ፡— በእኔና ፡ በአንተ ፡ መካ
ከል ፡ እነሆ ፡ ይህች ፡ ክምር ÷ እነሆም ፡ ያቆም
፶፪ ኋት ፡ ሐውልት ፤ እኔ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ይህችን ፡
ክምር ፡ እንዳላልፍ ÷ አንተም ፡ ለክፋት ፡ ወደ ፡
እኔ ፡ ይህችን ፡ ክምርና ፡ ይህችን ፡ ሐውልት ፡
እንዳታልፋት ÷ ይህች ፡ ክምር ፡ ምስክር ፡ ናት ÷
፶፫ ይህችም ፡ ሐውልት ፡ ምስክር ፡ ናት ። የአብርሃም ፡
አምላክ ፡ የናኮርም ፡ አምላክ ፡ የአባታቸውም ፡
አምላክ ፡ በእኛ ፡ መካከል ፡ ይፍረድ ። ያዕቆብም ፡
በአባቱ ፡ በይስሐቅ ፡ ፍርሃት ፡ ማለ ። ያዕቆብም ፡ ፶፬
በተራራው ፡ ላይ ፡ መሥዋዕትን ፡ ሠዋ ÷ ወን
ድሞቹንም ፡ እንጀራ ፡ እንዲበሉ ፡ ጠራ ፤ እነር
ሱም ፡ እንጀራን ፡ በሉ ÷ በዚያም ፡ በተራራ ፡
አደሩ ። ላባም ፡ ማልዶ ፡ ተነሥቶ ፡ ወንዶቹ ፶፭
ንና ፡ ሴቶቹን ፡ ልጆቹን ፡ ሳመ ፡ ባረካቸውም ፤
ላባም ፡ ተመልሶ ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ሄደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

ያዕቆብም ፡ መንገዱን ፡ ሄደ ÷ የእግዚአብ ፩
ሔር ፡ መላእክትም ፡ ተገናኙት ። ያዕቆብም ፡ ፪
ባያቸው ፡ ጊዜ ፡— እነዚህ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ሠራዊት ፡ ናቸው ፡ አለ ፤ የዚያንም ፡ ስፍራ ፡
ስም ፡ መሃናይም ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።

ያዕቆብም ፡ ወደ ፡ ወንድሙ ፡ ወደ ፡ ዔሳው ፡ ፫
ወደ ፡ ሴይር ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ ኤዶም ፡ አገር ፡
ከፊቱ ፡ መልእክተኞችን ፡ ላከ ፤ እንዲህም ፡ ፬
ብሎ ፡ አዘዛቸው ፡— ለጌታዬ ፡ ለዔሳው ፡— ባሪ
ያህ ፡ ያዕቆብ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡ ብላችሁ ፡ ንገሩት ፡—
በላባ ፡ ዘንድ ፡ በስደት ፡ ተቀመጥሁ ፤ እስከ ፡
አሁን ፡ ድረስ ፡ ቆየሁ ፤ ላሞችንም ፡ አህዮች ፭
ንም ፡ በጎችንም ፡ ወንዶች ፡ ባሪያዎችንም ፡
ሴቶች ፡ ባሪያዎችንም ፡ አገኘሁ ፤ አሁንም ፡
በፊትህ ፡ ሞገስን ፡ አገኝ ፡ ዘንድ ፡ ለጌታዬ ፡ ለማ
ስታወቅ ፡ ላክሁ ። መልእክተኞቹም ፡ ወደ ፡ ፮
ያዕቆብ ፡ ተመልሰው ፡ እንዲህ ፡ አሉት ፡—ወደ ፡
ወንድምህ ፡ ወደ ፡ ዔሳው ፡ ሄደን ፡ ነበር ፤ እር
ሱም ፡ ደግሞ ፡ ሊቀበልህ ፡ ይመጣል ÷ ከእር
ሱም ፡ ጋር ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ አሉ ። ያዕ ፯
ቆብም ፡ እጅግ ፡ ፈርቶ ፡ ተጨነቀ ፤ ከእርሱም ፡
ጋር ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ መንጎችንም ፡ ላሞች
ንም ፡ ግመሎችንም ፡ በሁለት ፡ ወገን ፡ ከፈላ
ቸው ፤ እንዲህም ፡ አለ ፡— ዔሳው ፡ መጥቶ ፡ ፰
አንዱን ፡ ወገን ፡ የመታ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የቀረው ፡
ወገን ፡ ያመልጣል ። ያዕቆብም ፡ አለ ፡— የአ ፱
ባቴ ፡ የአብርሃም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ የአባቴም ፡
የይስሐቅ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡— ወደ ፡ ምድርህ ፡
ወደ ፡ ተወለድህበትም ፡ ስፍራ ፡ ተመለስ ÷ በጎነት
ንም ፡ አደርግልሃለሁ ፡ ያልኸኝ ፡ እግዚአብሔር ፡
ሆይ ፤ ለባሪያህ ፡ ከሠራኸው ፡ ከምሕረትህና ፡ ፲
ከእውነትህም ፡ ሁሉ ፡ ትንሽ ፡ስንኳ ፡ የማይገ
ባኝ ፡ ነኝ ፤ በትሬን ፡ ብቻ ፡ ይዤ ፡ ይህን ፡ ዮር
ዳኖስን ፡ ተሻግሬ ፡ ነበርና ÷ አሁን ፡ ግን ፡ የሁ
ለት ፡ ክፍል ፡ ሠራዊት ፡ ሆንሁ ። ከወንድሜ ፡ ፲፩
ከዔሳው ፡ እጅ ፡ አድነኝ ፤ መጥቶ ፡ እንዳያጠ
ፋኝ ÷ እናቶችንም ፡ ከልጆች ፡ ጋር ፡ እንዳያ
ጠፋ ፡ እኔ ፡ እፈራዋለሁና ። አንተም ፡— በእር ፲፪
ግጥ ፡ መልካም ፡ አደርግልሃለሁ ÷ ዘርህንም ፡
ከብዛቱ ፡ የተነሣ ፡ እንደማይቈጠር ፡ እንደ ፡
ባሕር ፡ አሸዋ ፡ አደርጋለሁ ፡ ብለህ ፡ ነበር ።

በዚያችም ፡ ሌሊት ፡ ከዚያው ፡ አደረ ። ከያ ፲፫
ዘውም ፡ ሁሉ ፡ ለወንድሙ ፡ ለዔሳው ፡ እጅ ፡

፲፬ መንሻን፡ አወጣ ፤ ሁለት ፡ መቶ ፡ እንስት ፡ ፍየሎችንና ፡ ሀያ ፡ የፍየል ፡ አውራዎችን ፥ ሁለት ፡ መቶ ፡ እንስት ፡ በጎችንና ፡ ሀያ ፡ የበግ ፡ አውራ ፲፭ ዎችን ፥ ሠላሳ ፡ የሚያጠቡ ፡ ግመሎችን ፡ ከግልገሎቻቸው ፡ ጋር ፥ አርባ ፡ ላም ፥ አሥር ፡ በሬ ፥ ሀያ ፡ እንስት ፡ አህያ ፥ አሥርም ፡ የአህያ ፲፮ ግልገሎችን ። መንጎቹንም ፡ በየወገኑ ፡ ከፍሎ ፡ በባሪያዎቹ ፡ እጅ ፡ አደረጋቸው ፤ ባሪያዎቹንም ፡— በፊቴ ፡ እለፉ ፡ መንጋውንና ፡ መንጋውንም ፡ አራርቁት ፡ አለ ።

፲፯ የፊተኛውንም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘዘው ፡— ወንድሜ ፡ ዔሳው ፡ ያገኘህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡— አንተ ፡ የማን ፡ ነህ ? ወዴትስ ፡ ትሄዳለህ ? በፊትህ ፡ ያለው ፡ ይህስ ፡ የማን ፡ ነው ? ብሎ ፡ የጠየቀ ፲፰ ህም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አንተ ፡— ለጌታዬ ፡ ለዔሳው ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ የሰደደው ፡ የባሪያህ ፡ የያዕቆብ ፡ ነው ፤ እርሱም ፡ ደግሞ ፡ ፲፱ እነሆ ፡ ከኋላችን ፡ ነው ፡ በለው ። እንዲሁም ፡ ሁለተኛውንና ፡ ሦስተኛውን ፡ ከመንጎችም ፡ በኋላ ፡ የሚሄዱትን ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ ብሎ ፡ አዘዘ ፡— ዔሳውን ፡ በገኘችሁት ፡ ጊዜ ፡ ይህንኑ ፡ ፳ ነገር ፡ ንገሩት ፤ እንዲህም ፡ በሉት ፡— እነሆ ፡ ባሪያህ ፡ ያዕቆብ ፡ ከኋላችን ፡ ነው ። በፊቴ ፡ በሚሄደው ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ እታረቀዋለሁ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ምናልባት ፡ ይራራልኛል ፡ ፊቱ ፳፩ ንም ፡ አያለሁ ፡ ብሎአልና ። እጅ ፡ መንሻው ፡ ከእርሱ ፡ ቀድሞ ፡ አለፈ ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ በዚያች ፡ ሌሊት ፡ በሰፈር ፡ አደረ ።

፳፪ በዚያች ፡ ሌሊትም ፡ ተነሣ ፥ ሁለቱን ፡ ሚስቶቹንና ፡ ሁለቱን ፡ ባሪያዎቹን ፡ አሥራ ፡ አንዱንም ፡ ልጆቹን ፡ ወስዶ ፡ የያቦቅን ፡ ወንዝ ፡ ተሻ ፳፫ ገረ ። ወሰዳቸውም ፡ ወንዙንም ፡ አሻገራቸው ፥ ፳፬ ከብቱንም ፡ ሁሉ ፡ አሻገረ ። ያዕቆብ ፡ ግን ፡ ለብቻው ፡ ቀረ ፤ አንድ ፡ ሰውም ፡ እስከ ፡ ንጋት ፡ ፳፭ ድረስ ፡ ይታገለው ፡ ነበር ። እንዳላሸነፈውም ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ የጭኑን ፡ ሹልዳ ፡ ነካው ፤ የያዕቆብም ፡ የጭኑ ፡ ሹልዳ ፡ ሲታገለው ፡ ደነዘዘ ። ፳፮ እንዲህም ፡ አለው ፡— ሊነጋ ፡ አቀላልቶአልና ፡ ልቀቀኝ ። እርሱም ፡— ካልባረክኸኝ ፡ አልለቅ ፳፯ ቅህም ፡ አለው ። እንዲህም ፡ አለው ፡— ስምህ ፡ ማን ፡ ነው ? እርሱም ፡— ያዕቆብ ፡ ነኝ ፡ አለው ። ፳፰ አለውም ፡— ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ስምህ ፡ እስራኤል ፡ ይባል ፡ እንጂ ፡ ያዕቆብ ፡ አይባል ፤ ከእግዚአብሔር ፡ ከሰውም ፡ ጋር ፡ ታግለህ ፡ አሸን ፳፱ ፈሃልና ። ያዕቆብም ፡— ስምህን ፡ ንገረኝ ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ። እርሱም ፡— ስሜን ፡ ለምን ፡ ትጠይቃለህ ? አለው ። በዚያም ፡ ስፍራ ፡ በረ ፴ ከው ። ያዕቆብም ፡— እግዚአብሔርን ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ አየሁ ፥ ሰውነቴም ፡ ድና ፡ ቀረች ፡ ሲል ፡ የዚያን ፡ ቦታ ፡ ስም ፡ ጵኒኤል ፡ ብሎ ፡ ጠራው ። ፴፩ ጵኒኤልንም ፡ ሲያልፍ ፡ ፀሐይ ፡ ወጣችበት ፥ እርሱም ፡ በጭኑ ፡ ምክንያት ፡ ያነክስ ፡ ነበር ። ፴፪ ስለዚህም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ የወርችን ፡ ሹልዳ ፡ አይበሉም ፤ የያዕቆብን ፡ ጭን ፡ ይዞ ፡ የወርችን ፡ ሹልዳ ፡ አደንዝዞአልና ።

ቍ. ፴ ፤ ጵኒኤል ፡ የሚለውን ፡ ቃል ፡ የግእዝ ፡ መጽሐፍ ፡ ራእየ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይለዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፫ ።

፩ ያዕቆብም ፡ ዓይኑን ፡ አነሣ ፥ እነሆም ፡ ዔሳውን ፡ ሲመጣ ፡ አየው ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ ልጆቹንም ፡ ከፍሎ ፡ ወደ ፡ ልያና ፡ ወደ ፡ ራሔል ፡ ወደ ፡ ሁለቱም ፡ ባሪያዎች ፡ አደረጋ ፪ ቸው ፤ ባሪያዎችንና ፡ ልጆቻቸውንም ፡ በፊት ፡ አደረገ ፥ ልያንና ፡ ልጆችዋንም ፡ በኋለኛው ፡ ስፍራ ፥ ራሔልንና ፡ ዮሴፍንም ፡ ከሁሉ ፡ በኋላ ፡ ፫ አደረገ ። እርሱም ፡ በፊታቸው ፡ አለፈ ፤ ወደ ፡ ወንድሙም ፡ እስኪደርስ ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ፬ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ሰገደ ። ዔሳውም ፡ ሊገናኘው ፡ ሮጠ ፥ አንገቱንም ፡ አቅፎ ፡ ሳመው ፤ ተላቀ ፭ ሱም ። ዓይኑንም ፡ አነሣና ፡ ሴቶችንና ፡ ልጆችን ፡ አየ ፥ እንዲህም ፡ አለ ፡— እነዚህ ፡ ምኖችህ ፡ ናቸው ? እርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡ ለእኔ ፡ ለባሪያህ ፡ የሰጠኝ ፡ ልጆች ፡ ናቸው ፡ አለ ። ፮ ሴቶች ፡ ባሪያዎችም ፡ ከልጆቻቸው ፡ ጋር ፡ ቀር ፯ በው ፡ ሰገዱ ፤ ደግሞም ፡ ልያና ፡ ልጆችዋ ፡ ቀርበው ፡ ሰገዱ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ዮሴፍና ፡ ፰ ራሔል ፡ ቀርበው ፡ ሰገዱ ። እርሱም ፡— ያገኘሁት ፡ ይህ ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ ምንህ ፡ ነው ? አለ ። እርሱም ፡— በጌታዬ ፡ ፊት ፡ሞገስን ፡ ፱ አገኝ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ አለ ። ዔሳውም ፡— ለእኔ ፡ ብዙ ፡ አለኝ ፤ ወንድሜ ፡ ሆይ ፥ የአንተ ፡ ለአንተ ፡ ፲ ይሁን ፡ አለ ። ያዕቆብም ፡ አለ ፡— እንደዚህ ፡ አይደለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በፊትህ ፡ ሞገስን ፡ አግኝቼ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እጅ ፡ መንሻዬን ፡ ተቀበለኝ ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ፊት ፡ እንደሚያይ ፡ ፊትህን ፡ አይቼአለሁና ፥ በቸርነትም ፡ ተቀብለ ፲፩ ኸኛልና ። ይህችንም ፡ ያመጣሁልህን ፡ በረከቴን ፡ ተቀበል ፤ እግዚአብሔር ፡ በቸርነት ፡ ሰጥቶኛልና ፥ ለእኔም ፡ ብዙ ፡ አለኝና ። እስኪቀበ ፲፪ ለውም ፡ ድረስ ፡ ዘበዘበው ። እርሱም ፡— ተነሣና ፡ እንሂድ ፥ እኔም ፡ በፊትህ ፡ እሄዳለሁ ፡ ፲፫ አለ ። እርሱም ፡ አለው ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ ልጆቹ ፡ ደካሞች ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ታውቃለህ ፤ በጎችና ፡ ላሞችም ፡ ግልገሎቻቸውን ፡ ያጠባሉ ፤ ሰዎችም ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ በችኮላ ፡ የነዱአቸው ፡ ፲፬ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከብቶቹ ፡ ሁሉ ፡ ይሞታሉ ። ጌታዬ ፡ ከባሪያው ፡ ፊት ፡ ቀድሞ ፡ ይለፍ ፤ እኔም ፡ ወደ ፡ ሴይር ፡ ከጌታዬ ፡ ዘንድ ፡ እስክደርስ ፡ ድረስ ፡ ከፊቴ ፡ ባሉት ፡ በእንስሳቱ ፡ እርምጃና ፡ በሕፃናቱ ፡ እርምጃ ፡ መጠን ፡ በዝግታ ፡ እከተላለሁ ። ፲፭ ዔሳውም ፡— ከእኔ ፡ ጋር ፡ ካሉት ፡ ሰዎች ፡ ከፍዬ ፡ ልተውልህን ? አለ ። እርሱም ፡— ይህ ፡ ለምንድር ፡ ነው ? በጌታዬ ፡ ዘንድ ፡ ሞገስን ፡ ማግ ፲፮ ኘት ፡ ይበቃኛል ፡ አለ ። ዔሳውም ፡ በዚያን ፡ ቀን ፡ ፲፯ ወደ ፡ ሴይር ፡ መንገዱን ፡ ተመለሰ ። ያዕቆብ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ሱኮት ፡ ሄደ ፤ በዚያም ፡ ለእርሱ ፡

ቤትን ፡ ሠራ ፥ ለከብቶችም ፡ ዳሶችን ፡ አደረገ ፤
ስለዚህም ፡ የዚያን ፡ ቦታ ፡ ስም ፡ ሱኮት ፡ ብሎ ፡
ጠራው ።

፲፰ ፤ ያዕቆብም ፡ ከሁለት ፡ ወንዞች ፡ መካከል ፡ በተ
መለሰ ፡ ጊዜ ፡ በከንዓን ፡ ምድር ፡ ወዳለችው ፡
ወደ ፡ ሴኬም ፡ ከተማ ፡ በደኅንነት ፡ መጣ ፤ በከ
፲፱ ፤ ተማይቱም ፡ ፊት ፡ ሰፈረ ። ድንኳኑን ፡ ተክሎ
በት ፡ የነበረውንም ፡ የእርሻውን ፡ ክፍል ፡ ከሴ
ኬም ፡ አባት ፡ ከኤሞር ፡ ልጆች ፡ በመቶ ፡ በጎች ፡
፳ ፤ ገዛው ። በዚያም ፡ መሠውያውን ፡ አቆመ ፥ ያንም ፡
ኤል ፡ ኤሎሄ ፡ እስራኤል ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፬ ።

፩ ፤ ለያዕቆብ ፡ የወለደችለት ፡ የልያ ፡ ልጅ ፡ ዲናም ፡
የዚያን ፡ አገር ፡ ሴቶች ፡ ልጆችን ፡ ለማየት ፡
፪ ፤ ወጣች ። የአገሩ ፡ አለቃ ፡ የኤዊያዊ ፡ ሰው ፡
የኤሞር ፡ ልጅ ፡ ሴኬም ፡ አያት ፤ ወሰዳትም ፡
፫ ፤ ከእርስዋም ፡ ጋር ፡ ተኛ ፥ አስነወራትም ። ልቡ
ናውም ፡ በያዕቆብ ፡ ልጅ ፡ በዲና ፡ ፍቅር ፡ ተነ
ደፈ ፥ ብላቴናይቱንም ፡ ወደዳት ፥ ልብዋንም ፡
፬ ፤ ደስ ፡ በሚያሰኛት ፡ ነገር ፡ ተናገራት ። ሴኬ
ምም ፡ አባቱን ፡ ኤሞርን ፡— ይህችን ፡ ብላቴና ፡
፭ ፤ አጋባኝ ፡ ብሎ ፡ ነገረው ። ያዕቆብም ፡ ልጁን ፡
ዲናን ፡ እንዳስነወራት ፡ ሰማ ፤ ልጆቹም ፡ ከከ
ብቶቻቸው ፡ ጋር ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ነበሩ ፤ ያዕ
፮ ፤ ቆብም ፡ እስኪመጡ ፡ ድረስ ፡ ዝም ፡ አለ ። የሴ
ኬም ፡ አባት ፡ ኤሞርም ፡ ይነግረው ፡ ዘንድ ፡
፯ ፤ ወደ ፡ ያዕቆብ ፡ ወጣ ። የያዕቆብም ፡ ልጆች ፡ ይህ
ንን ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ከምድረ ፡ በዳ ፡ መጡ ፤
የያዕቆብን ፡ ልጅ ፡ በመተኛቱ ፡ በእስራኤል ፡
ላይ ፡ ስንፍናን ፡ ስላደረገ ፡ አዘኑ ፥ እጅግም ፡
፰ ፤ ተቈጡ ፤ እንዲህ ፡ አይደረግምና ። ኤሞርም ፡
እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ነገራቸው ፡— ልጄ ፡ ሴኬም ፡
በልጃችሁ ፡ ፍቅር ፡ ልቡ ፡ ተነድፎአልና ፡ ሚስት ፡
እንድትሆነው ፡ እባካችሁ ፡ እርስዋን ፡ ስጡት ።
፱ ፤ ጋብቻችም ፡ ሁኑን ፤ ሴቶች ፡ ልጆቻችሁን ፡
ስጡን ፥ እናንተም ፡ የእኛን ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡
፲ ፤ ውሰዱ ። ከእኛም ፡ ጋር ፡ ተቀመጡ ፥ ምድሪ
ቱም ፡ በፊታችሁ ፡ ናት ፤ ኑሩባት ፥ ነግዱም ፥
፲፩ ፤ ግዙአትም ። ሴኬምም ፡ አባትዋንና ፡ ወንድ
ሞችዋን ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— በፊታችሁ ፡ ሞገ
፲፪ ፤ ስን ፡ ባገኝ ፡ የምትሉኝን ፡ እሰጣለሁ ። ብዙ ፡
ማጫና ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ አምጣ ፡ በሉኝ ፥ በነገ
ራችሁኝም ፡ መጠን ፡ እሰጣለሁ ፤ ይህችን ፡ ብላ
፲፫ ፤ ቴና ፡ ግን ፡ አጋቡኝ ። የያዕቆብም ፡ ልጆች ፡
ለሴኬምና ፡ ለአባቱ ፡ ለኤሞር ፡ በተንኰል ፡
መለሱ ፥ እኅታቸውን ፡ ዲናን ፡ አርክሶአታልና ፤
፲፬ ፤ እንዲህም ፡ አሉአቸው ፡— እኅታችንን ፡ ላልተ
ገረዘ ፡ ሰው ፡ ለመስጠት ፡ ይህንን ፡ ነገር ፡ እናደ
ርግ ፡ ዘንድ ፡ አይቻለንም ፤ ይህ ፡ ነውር ፡ ይሆ
፲፭ ፤ ንብናልና ። እንደ ፡ እኛ ፡ ሆናችሁ ፡ ወንዶቻ
ችሁን ፡ ሁሉ ፡ ብትገርዙ ፡ በዚህ ፡ ብቻ ፡ እሺ ፡
፲፮ ፤ እንላችኋለን ፤ ሴቶች ፡ ልጆቻችንን ፡ እንሰጣ
ችኋለን ፥ የእናንተንም ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ እንወ
ስዳለን ፤ አንድ ፡ ሕዝብም ፡ ሆነን ፡ ከእናንተ ፡
ጋር ፡ እንኖራለን ። ትገረዙ ፡ ዘንድ ፡ እኛን ፡ ፲፯ ፤
ባትሰሙ ፡ ግን ፡ ልጃችንን ፡ ይዘን ፡ እንሄዳለን ።
ነገራቸውም ፡ በኤሞር ፡ ልጅ ፡ በሴኬምና ፡ ፲፰ ፤
በኤሞር ፡ ዘንድ ፡ የተወደደ ፡ ሆነ ። ብላቴና ፲፱ ፤
ውም ፡ ያሉትን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ አልዘገየም ፥
የያዕቆብን ፡ ልጅ ፡ ወድዶአልና ፤ እርሱም ፡ በአ
ባቱ ፡ ቤት ፡ ካሉት ፡ ሁሉ ፡ የከበረ ፡ ነበረ ።
ኤሞርና ፡ ሴኬም ፡ ልጁም ፡ ወደ ፡ ከተማቸው ፡ አደ ፳ ፤
ባባይ ፡ ገቡ ፥ ለከተማቸውም ፡ ሰዎች ፡ እንዲህ ፡
ብለው ፡ ነገሩ ፡— እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ ፳፩ ፤
የሰላም ፡ ሰዎች ፡ ናቸው ፤ በምድራችን ፡ ይቀ
መጡ ፥ ይነግዱባትም ፥ እነሆም ፡ ምድሪቱ ፡
ሰፊ ፡ ናት ፤ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ እንውሰድ ፥
ለእነርሱም ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችንን ፡ እንስጥ ።
ነገር ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ሕዝብ ፡ ሆነን ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ፳፪ ፤
ይቀመጡ ፡ ዘንድ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ብቻ ፡ እሺ ፡
ይሉናል ፤ እነርሱ ፡ እንደ ፡ ተገረዙ ፡ ወንዶቻች
ንን ፡ ሁሉ ፡ ብንገርዝ ። ከብቶቻቸውም ፡ ያላቸ ፳፫ ፤
ውም ፡ ሁሉ ፡ እንስሶቻቸውም ፡ ሁሉ ፡ ለእኛ ፡
አይደሉምን ? በዚህ ፡ ነገር ፡ ብቻ ፡ እሺ ፡ ያልና
ቸው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ይቀመጣሉ ።
ከከተማይቱም ፡ አደባባይ ፡ የሚወጡ ፡ ሁሉ ፡ ፳፬ ፤
ኤሞርንና ፡ ልጁን ፡ ሴኬምን ፡ እሺ ፡ አሉ ፤ ከከ
ተማይቱ ፡ አደባባይ ፡ የሚወጡት ፡ ወንዶች ፡
ሁሉ ፡ ተገረዙ ። ሦስተኛም ፡ ቀን ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ፳፭ ፤
እጅግ ፡ ቈስለው ፡ ሳሉ ፥ የዲና ፡ ወንድሞች ፡
የያዕቆብ ፡ ልጆች ፡ ስምዖንና ፡ ሌዊ ፡ እየራሳ
ቸው ፡ ሰይፋቸውን ፡ ይዘው ፡ ሳይፈሩ ፡ ወደ ፡
ከተማ ፡ ገቡ ፥ ወንዱንም ፡ ሁሉ ፡ ገደሉ ፤ ኤሞ ፳፮ ፤
ርንና ፡ ልጁን ፡ ሴኬምንም ፡ በሰይፍ ፡ ገደሉ ፥
እኅታቸውን ፡ ዲናንም ፡ ከሴኬም ፡ ቤት ፡ ይዘው ፡
ወጡ ። የያዕቆብም ፡ ልጆች ፡ እኅታቸውን ፡ ፳፯ ፤
ዲናን ፡ ስለ ፡ አረከሱአት ፡ ወደ ፡ ሞቱት ፡ ገብተው ፡
ከተማይቱን ፡ ዘረፉ ፤ በጎቻቸውንም ፡ ላሞቻቸ ፳፰ ፤
ውንም ፡ አህዮቻቸውንም ፡ በውጭም ፡ በከተ
ማም ፡ ያለውን ፡ ወሰዱ ። ሀብታቸውን ፡ ሁሉ ፡ ፳፱ ፤
ሕፃናቶቻቸውንና ፡ ሴቶቻቸውንም ፡ ሁሉ ፡
ማረኩ ፥ በቤት ፡ ያለውንም ፡ ሁሉ ፡ ዘረፉ ። ያዕ ፴ ፤
ቆብም ፡ ሌዊንና ፡ ስምዖንን ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—
በዚች ፡ አገር ፡ በሚኖሩ ፡ በከነዓናውያንና ፡ በፌ
ርዛውያን ፡ ሰዎች ፡ የተጠላሁ ፡ ታደርጉኝ ፡
ዘንድ ፡ እኔን ፡ አስጨነቃችሁኝ ፤ እኔ ፡ በቍጥር ፡
ጥቂት ፡ ነኝ ፤ እነርሱ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ይሰበሰቡና ፡
ይመቱኛል ፤ እኔም ፡ ከወገኔ ፡ ጋር ፡ እጠፋለሁ ።
እነርሱም ፡—በጋለሞታ ፡ እንደሚደረግ ፡ በእኅ ፴፩ ፤
ታችን ፡ ያደርግባትን ? አሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፭ ።

እግዚአብሔርም ፡ ያዕቆብን ፡ አለው ፡— ተነ ፩ ፤
ሥተህ ፡ ወደ ፡ ቤቴል ፡ ውጣ ፥ በዚያም ፡ ኑር ፤
ከወንድምህ ፡ ከዔሳው ፡ ፊት ፡ በሸሸህ ፡ ጊዜ ፡
ለተገለጠልህ ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ መሠውያ
ውን ፡ አድርግ ። ያዕቆብም ፡ ለቤተ ፡ ሰቡና ፡ ፪ ፤

ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ላሉት ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— እንግዶቹን ፡ አማልክት ፡ ከመካከላችሁ ፡ አስወግዱ ፥ ንጹሐንም ፡ ሁኑ ፥ ልብሳችሁንም ፡ ለውጡ ፤ ፫ ተነሥተንም ፡ ወደ ፡ ቤቴል ፡ እንውጣ ፤ በዚያም ፡ በመከራዬ ፡ ጊዜ ፡ ለሰማኝ ፥ በሄድሁበትም ፡ መንገድ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ለነበረው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠውያን ፡ አደርጋለሁ ። ፬ በእጃቸው ፡ ያሉትንም ፡ እንግዶችን ፡ አማልክት ፡ ሁሉ ፡ በጆሮአቸውም ፡ ያሉትን ፡ ጉትቻች ፡ ለያዕቆብ ፡ ሰጡት ፤ ያዕቆብም ፡ በሴኬም ፡ አጠገብ ፡ ካለችው ፡ የአድባር ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ ቀበራቸው ። ፭ ተነሥተውም ፡ ሄዱ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ፍርሃት ፡ በዙሪያቸው ፡ ባሉት ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ወደቀ ፥ የያዕቆብንም ፡ ልጆች ፡ ለማሳደድ ፡ አልተከተሉአቸውም ። ፮ ያዕቆብም ፥ እርሱ ፡ ከእርሱ ፡ ጋርም ፡ የነበሩት ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፥ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ወዳለችው ፡ ወደ ፡ ሎዛ ፡ መጡ ፤ እርስዋም ፡ ቤቴል ፡ ናት ። ፯ በዚያም ፡ መሠውያውን ፡ ሠራ ፥ የዚያንም ፡ ቦታ ፡ ስም ፡ ኤልቤቴል ፡ ብሎ ፡ ጠራው ፤ እርሱ ፡ ከወንድሙ ፡ ፊት ፡ በሸሸበት ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚያ ፡ ተገልጦለት ፡ ነበርና ። ፰ የርብቃ ፡ ሞግዚት ፡ ዲቦራም ፡ ሞተች ፥ በቤቴልም ፡ ከአድባር ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ ተቀበረች ፤ ስሙም ፡ አሎንባኩት ፡ ተብሎ ፡ ተጠራ ።

፱ እግዚአብሔርም ፡ ለያዕቆብ ፡ ከሁለት ፡ ወንዞች ፡ መካከል ፡ ከሶርያ ፡ ከተመለሰ ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ተገለጠለት ፥ ባረከውም ። ፲ እግዚአብሔርም ፡— ስምህ ፡ ያዕቆብ ፡ ነው ፤ ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ ስምህ ፡ ያዕቆብ ፡ ተብሎ ፡ አይጠራ ፥ ስምህ ፡ እስራኤል ፡ ይበል ፡ እንጂ ፡ አለ ፤ ስሙንም ፡ እስራኤል ፡ ብሎ ፡ ጠራው ። ፲፩ እግዚአብሔርም ፡ አለው ፡— ሁሉን ፡ ቻይ ፡ አምላክ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ ብዛ ፥ ተባዛም ፤ ሕዝብና ፡ የአሕዛብ ፡ ማኅበር ፡ ከአንተ ፡ ይሆናል ፥ ነገሥታትም ፡ ከጕልበትህ ፡ ይወጣሉ ። ፲፪ ለአብርሃምና ፡ ለይስሐቅም ፡ የሰጠኋትን ፡ ምድር ፡ ለአንተ ፡ እሰጣለሁ ፥ ከአንተም ፡ በኋላ ፡ ለዘርህ ፡ ምድሪቱን ፡ እሰጣለሁ ። ፲፫ እግዚአብሔርም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ከተነጋገረበት ፡ ስፍራ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ወጣ ። ፲፬ ያዕቆብም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በተነጋገረበት ፡ ቦታ ፡ የድንጋይ ፡ ሐውልት ፡ ተከለ ፤ የመጠጥ ፡ መሥዋዕትንም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ አፈሰሰ ፥ ዘይትንም ፡ አፈሰሰበት ። ፲፭ ያዕቆብም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የተነጋገረበትን ፡ ያን ፡ ቦታ ፡ ቤቴል ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።

፲፮ ከቤቴልም ፡ ተነሡ ፤ ወደ ፡ ኤፍራታም ፡ ሊደርሱ ፡ ጥቂት ፡ ሲቀራቸው ፡ ራሔልን ፡ ምጥ ፡ ያዛት ፥ በምጡም ፡ ተጨነቀች ። ፲፯ ምጡም ፡ በስጨነቃት ፡ ጊዜ ፡ አዋላጂቱ ፡— አትፍሪ ፥ ይኸኛው ፡ ደግሞ ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ይሆንሻልና ፡ አለቻት ። ፲፰ እርስዋም ፡ ስትሞት ፡ ነፍስዋ ፡ በምትወጣበት ፡ ጊዜ ፡ ስሙን ፡ ቤንኦኒ ፡ ብላ ፡ ጠራችው ፤ አባቱ ፡ ግን ፡ ብንያም ፡ አለው ። ፲፱ ራሔልም ፡ ሞተች ፥ ወደ ፡ ኤፍራታ ፡ በምትወስድም ፡ መንገድ ፡ ተቀበረች ፤ እርስዋም ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፡ ናት ። ፳ ያዕቆብም ፡ በመቃብርዋ ፡ ላይ ፡ ሐውልት ፡ አቆመ ፤ እርሱም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ የራሔል ፡ የመቃብርዋ ፡ ሐውልት ፡ ነው ። ፳፩ እስራኤልም ፡ ከዚያ ፡ ተነሣ ፥ ድንኳኑንም ፡ ከጋዴር ፡ ግንብ ፡ በስተ ፡ ወዲያ ፡ ተከለ ። ፳፪ እስራኤልም ፡ በዚያች ፡ አገር ፡ በተቀመጠ ፡ ጊዜ ፡ ሮቤል ፡ ሄደ ፡ የአባቱንም ፡ ቁባት ፡ ባላን ፡ ተገናኛት ፤ እስራኤልም ፡ ሰማ ።

የያዕቆብም ፡ ልጆች ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ናቸው ፤ ፳፫ የልያ ፡ ልጆች ፤ የያዕቆብ ፡ በኵር ፡ ልጅ ፡ ሮቤል ፥ ስምዖን ፥ ሌዊ ፥ ይሁዳ ፥ ይሳኮር ፥ ዛብሎን ፤ ፳፬ የራሔል ፡ ልጆች ፤ ዮሴፍ ፥ ብንያም ፤ ፳፭ የራሔል ፡ ባሪያ ፡ የባላ ፡ ልጆችም ፤ ዳን ፥ ንፍታሌም ፤ ፳፮ የልያ ፡ ባሪያ ፡ የዘለፋ ፡ ልጆችም ፤ ጋድ ፥ አሴር ፤ እነዚህ ፡ በሁለቱ ፡ ወንዞች ፡ መካከል ፡ በሶርያ ፡ የተወለዱለት ፡ የያዕቆብ ፡ ልጆች ፡ ናቸው ። ፳፯ ያዕቆብም ፡ ወደ ፡ አባቱ ፡ ወደ ፡ ይስሐቅ ፡ አብርሃምና ፡ ይስሐቅ ፡ እንግዶች ፡ ሆነው ፡ ወደ ፡ ተቀመጡበት ፡ ወደ ፡ መምሬ ፡ ወደ ፡ ቂርያትአርባቅ ፡ እርስዋም ፡ ኬብሮን ፡ ወደምትባለው ፡ መጣ ።

፳፰ የይስሐቅም ፡ ዕድሜ ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ ዓመት ፡ ሆነ ። ፳፱ ይስሐቅም ፡ ነፍሱን ፡ ሰጠ ፥ ሞተም ፤ ሸምግሎ ፡ ዕድሜንም ፡ ጠግቦ ፡ ወደ ፡ ወገኖቹ ፡ ተከማቸ ፤ ልጆቹም ፡ ዔሳውና ፡ ያዕቆብ ፡ ቀበሩት ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፮ ።

፩ የዔሳው ፡ ትውልድ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ እርሱም ፡ ኤዶም ፡ ነው ። ፪ ዔሳው ፡ ከከነዓን ፡ ልጆች ፡ ሚስቶችን ፡ አገባ ፤ የኬጢያዊውን ፡ የዔሎንን ፡ ልጅ ፡ ዓዳን ፥ የኤዊያዊው ፡ የፅብዖን ፡ ልጅ ፡ ዓና ፡ የወለዳትን ፡ አህሊባማን ፥ ፫ የእስማኤልን ፡ ልጅ ፡ የነባዮትን ፡ እኅት ፡ ቤሴሞትን ። ፬ ዓዳ ፡ ለዔሳው ፡ ኤልፋዝን ፡ ወለደች ፤ ቤሴሞትም ፡ ራጉኤልን ፡ ወለደች ፤ ፭ አህሊባማም ፡ የዑስን ፥ የዕላምን ፥ ቆሬን ፡ ወለደች ፤ በከነዓን ፡ ምድር ፡ የተወለዱለት ፡ የዔሳው ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። ፮ ዔሳውም ፡ ሚስቶቹን ፡ ወንዶች ፡ ልጆቹንና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቹን ፡ ቤተ ፡ ሰቡንም ፡ ሁሉ ፡ ከብቱንም ፡ ሁሉ ፡ እንስሶቹንም ፡ ሁሉ ፡ በከነዓንም ፡ አገር ፡ ያገኘውን ፡ ሁሉ ፡ ይዞ ፡ ከወንድሙ ፡ ከያዕቆብ ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ አገር ፡ ሄደ ። ፯ ከብታቸው ፡ ስለ ፡ በዛ ፡ በአንድነት ፡ ይቀመጡ ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉም ፤ በእንግድነት ፡ የተቀመጡባትም ፡ ምድር ፡ ከከብታቸው ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ልትበቃቸው ፡ አልቻለችም ። ፰ ዔሳውም ፡ በሴይር ፡ ተራራ ፡ ተቀመጠ ፤ ዔሳውም ፡ ኤዶም ፡ ነው ።

፱ በሴይር ፡ ተራራ ፡ የሚኖሩ ፡ የኤዶማውያን ፡ አባት ፡ የዔሳው ፡ ትውልድም ፡ ይህ ፡ ነው ። ፲ የዔሳው ፡ ልጆች ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የዔሳው ፡

ሚስት ፡ የዓዳ ፡ ልጅ ፡ ኤልፋዝ ፤ የዔሳው ፡
፲፩፤ ሚስት ፡ የቤሴሞት ፡ ልጅ ፡ ራጉኤል ። የኤልፋ
ዝም ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ቴማን ፥
፲፪፤ ኦማር ፥ ስፎ ፥ ጎቶም ፥ ቄኔዝ ። ቲምናዕም ፡
ለዔሳው ፡ ልጅ ፡ ለኤልፋዝ ፡ የጭን ፡ ገረድ ፡
ነበረች ፥ አማሌቅንም ፡ ለኤልፋዝ ፡ ወለደች
ለት ፤ የዔሳው ፡ ሚስት ፡ የዓዳ ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡
፲፫፤ ናቸው ። የራጉኤልም ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡
ናቸው ፤ ናሖት ፥ ዛራ ፥ ሣማ ፥ ሚዛህ ፤ እነዚህም ፡
የዔሳው ፡ ሚስት ፡ የቤሴሞት ፡ ልጆች ፡ ናቸው ።
፲፬፤ የፅብዖን ፡ ልጅ ፡ የዓና ፡ ልጅ ፡ የዔሳው ፡ ሚስት ፡
የአህሊባማ ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ለዔሳ
ውም ፡ የዑስን ፥ የዕላማን ፥ ቆሬን ፡ ወለደች ።
፲፭፤ የዔሳው ፡ ልጆች ፡ አለቆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤
ለዔሳው ፡ የበኵር ፡ ለኤልፋዝ ፡ ልጆች ፤ ቴማን ፡
አለቃ ፥ ኦማር ፡ አለቃ ፥ ስፎ ፡ አለቃ ፥ ቄኔዝ ፡
፲፮፤ አለቃ ፥ ቆሬ ፡ አለቃ ፥ ጎቶም ፡ አለቃ ፥ አማሌቅ ፡
አለቃ ፤ በኤዶም ፡ ምድር ፡ የኤልፋዝ ፡ አለ
ቆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ እነዚህ ፡ የዓዳ ፡ ልጆች ፡
፲፯፤ ናቸው ። የዔሳው ፡ ልጅ ፡ የራጉኤል ፡ ልጆች ፡
እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ናሖት ፡ አለቃ ፥ ዛራ ፡ አለቃ ፥
ሣማ ፡ አለቃ ፥ ሚዛህ ፡ አለቃ ፤ በኤዶም ፡ ምድር ፡
የራጉኤል ፡ ልጆች ፡ አለቆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤
እነዚህም ፡ የዔሳው ፡ ሚስት ፡ የቤሴሞት ፡
፲፰፤ ልጆች ፡ ናቸው ። የዔሳው ፡ ሚስት ፡ የአህሊ
ባማ ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ የዑስ ፡ አለቃ ፥
የዕላማ ፡ አለቃ ፥ ቆሬ ፡ አለቃ ፤ የዔሳው ፡ ሚስት ፡
የዓና ፡ ልጅ ፡ የአህሊባማ ፡ አለቆች ፡ እነዚህ ፡
፲፱፤ ናቸው ። የዔሳው ፡ ልጆችና ፡ አለቆቻቸው ፡
እነዚህ ፡ ናቸው ፤ እርሱም ፡ ኤዶም ፡ ነው ።
፳፤ በዚያች ፡ አገር ፡ የተቀመጡ ፡ የሖሪው ፡ የሴ
ይር ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ሎጣን ፥ ሦባል ፥
፳፩፤ ፅብዖን ፥ ዓና ፥ ዲሶን ፥ ኤጽር ፥ ዲሳን ፤ እነዚህ ፡
በኤዶም ፡ ምድር ፡ የሖሪው ፡ የሴይር ፡ ልጆች ፡
፳፪፤ አለቆች ፡ ናቸው ። የሎጣን ፡ ልጆችም ፡ ሖሪ ፥
ሄማም ፡ ናቸው ፤ የሎጣንም ፡ እኅት ፡ ቲምናዕ ፡
፳፫፤ ናት ። የሦባል ፡ ልጆችም ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤
ዓልዋን ፥ ማኔሐት ፥ ዔባል ፥ ስፎ ፥ አውናም ።
፳፬፤ የፅብዖን ፡ ልጆችም ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ አያ ፥
ዓና ፤ ይህም ፡ ዓና ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የአባቱን ፡
የፅብዖንን ፡ አህዮች ፡ ሲጠብቅ ፡ ፍልውኆችን ፡
፳፭፤ ያገኘ ፡ ነው ። የዓና ፡ ልጆችም ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤
፳፮፤ ዲሶን ፥ አህሊባማም ፡ የዓና ፡ ሴት ፡ ልጅ ። የዲሶ
ንም ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ሔምዳን ፥ ኤስ
፳፯፤ ባን ፥ ይትራን ፥ ክራን ። የኤጽር ፡ ልጆችም ፡
እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ቢልሐን ፥ ዛዕዋን ፥ ዓቃን ።
፳፰፤ የዲሳን ፡ ልጆችም ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ዑፅ ፥
፳፱፤ አራን ። የሖሪ ፡ አለቆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤
ሎጣን ፡ አለቃ ፥ ሦባል ፡ አለቃ ፥ ፅብዖን ፡ አለቃ ፥
፴፤ ዓና ፡ አለቃ ፥ ዲሶን ፡ አለቃ ፥ ኤጽር ፡ አለቃ ፥
ዲሳን ፡ አለቃ ፤ በሴይር ፡ ምድር ፡ አለቆች ፡ የሆኑ ፡
የሖሪ ፡ አለቆቹ ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።
፴፩፤ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ከመ
ኖሩ ፡ በፊት ፡ በኤዶም ፡ አገር ፡ የነገሡ ፡ ነገሥ
ታት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። በኤዶምም ፡ የቢዖር ፡ ፴፪፤
ልጅ ፡ ባላቅ ፡ ነገሠ ፤ የከተማውም ፡ ስም ፡ ዲን
ሃባ ፡ ናት ። ባላቅም ፡ ሞተ ፥ በስፍራውም ፡ ፴፫፤
የባሶራው ፡ የዛራ ፡ ልጅ ፡ ኢዮባብ ፡ ነገሠ ።
ኢዮባብም ፡ ሞተ ፥ በስፍራውም ፡ የቴማኒው ፡ ፴፬፤
አገር ፡ ሑሳም ፡ ነገሠ ። ሑሳምም ፡ ሞተ ፥ በስፍራ ፴፭፤
ውም ፡ የምድያምን ፡ ሰዎች ፡ በሞዓብ ፡ሜዳ ፡
የመታ ፡ የባዳድ ፡ ልጅ ፡ ሃዳድ ፡ ነገሠ ፤ የከተማ
ውም ፡ ስም ፡ ዓዊት ፡ ተባለ ። ሃዳድም ፡ ሞተ ፥ በስ ፴፮፤
ፍራውም ፡ የመሥሬቃው ፡ ሠምላ ፡ ነገሠ ። ሠም ፴፯፤
ላም ፡ ሞተ ፥ በስፍራውም ፡ በወንዝ ፡ አጠገብ ፡
ካለችው ፡ ከርሆቦት ፡ ሳኡል ፡ ነገሠ ። ሳኡልም ፡ ፴፰፤
ሞተ ፥ በስፍራውም ፡ የዓክቦር ፡ ልጅ ፡ በአልሐ
ናን ፡ ነገሠ ። የዓክቦር ፡ ልጅ ፡ በአልሐናንም ፡ ፴፱፤
ሞተ ፥ በስፍራውም ፡ ሃዳር ፡ ነገሠ ፤ የከተማ
ውም ፡ ስም ፡ ፋዑ ፡ ነው ፤ ሚስቱም ፡ የሜዛሃብ ፡
ልጅ ፡ መጥሬድ ፡ የወለደቻት ፡ መሄጣብኤል ፡
ትባላለች ።
የዔሳውም ፡ የአለቆቹ ፡ ስም ፡ በወገናቸው ፡ ፵፤
በስፍራቸው ፡ በስማቸውም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ቲም
ናዕ ፡ አለቃ ፥ ዓልዋ ፡ አለቃ ፥ የቴት ፡ አለቃ ፥
አህሊባማ ፡ አለቃ ፥ ኤላ ፡ አለቃ ፥ ፊኖን ፡ አለቃ ፥ ፵፩፤
ቄኔዝ ፡ አለቃ ፥ ቴማን ፡ አለቃ ፥ ሚብሳር ፡ አለቃ ፥ ፵፪፤
መግዲኤል ፡ አለቃ ፥ ዒራም ፡ አለቃ ፥ እነዚህ ፡ ፵፫፤
በግዛታቸው ፡ ምድር ፡ በየመኖሪያቸው ፡ የኤ
ዶም ፡ አለቆች ፡ ናቸው ። የኤዶማውያን ፡
አባት ፡ ይህ ፡ ዔሳው ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፯ ።

ያዕቆብም ፡ አባቱ ፡ በስደት ፡ በኖረበት ፡ አገር ፡ ፩፤
በከነዓን ፡ ምድር ፡ ተቀመጠ ። የያዕቆብም ፡ ፪፤
ትውልድ ፡ ይህ ፡ ነው ። ዮሴፍ ፡ የአሥራ ፡ ሰባት ፡
ዓመት ፡ ልጅ ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ከወንድሞቹ ፡ ጋር ፡
በጎችን ፡ ይጠብቅ ፡ ነበር ፤ እርሱም ፡ ከአባቱ ፡
ሚስቶች ፡ ከባላና ፡ ከዘለፋ ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ ሳለ ፡
ብላቴና ፡ ነበረ ፤ ዮሴፍም ፡ የክፋታቸውን ፡ ወሬ ፡
ወደ ፡ አባታቸው ፡ አመጣ ። እስራኤልም ፡ ዮሴ ፫፤
ፍን ፡ ከልጆቹ ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ይወደው ፡ ነበር ፥
እርሱ ፡ በሽምግልናው ፡ የወለደው ፡ ነበርና ፤
በብዙ ፡ ኅብር ፡ ያጌጠችም ፡ ቀሚስ ፡ አደረገ
ለት ። ወንድሞቹም ፡ አባታቸው ፡ ከልጆቹ ፡ ፬፤
ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ እንዲወደው ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ጠሉት ፥
በሰላም ፡ ይናገሩትም ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉም ።
ዮሴፍም ፡ ሕልምን ፡ አለመ ፥ ለወንድሞቹም ፡ ፭፤
ነገራቸው ፤ እነርሱም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ በብዙ ፡
ጠሉት ። እርሱም ፡ አላቸው ፡— እኔ ፡ ያለምሁ ፮፤
ትን ፡ ሕልም ፡ ስሙ ፤ እነሆ ፡ እኛ ፡ በእርሻ ፡ መካ ፯፤
ከል ፡ ነዶ ፡ ስናስር ፡ ነበርና ፥ እነሆም ፥ የእኔ ፡
ነዶ ፡ ቀጥ ፡ ብላ ፡ ቆመች ፤ የእናንተም ፡ ነዶች ፡
በዙሪያ ፡ ከብበው ፡ እነሆ ፡ ለእኔ ፡ ነዶ ፡ ሰገዱ ።
ወንድሞቹም ፡— በእኛ ፡ ላይ ፡ ልትነግሥብን ፡ ፰፤
ይሆን ? ወይስ ፡ ልትገዛ ፡ ይሆን ? አሉት ።
እንደ ፡ ገናም ፡ ስለ ፡ ሕልሙና ፡ ስለ ፡ ነገሩ ፡ ይል
ቁን ፡ ጠሉት ። ደግሞም ፡ ሌላ ፡ ሕልምን ፡ ፱፤

አለመ ፣ ለወንድሞቹም ፡ ነገራቸው ፣ እንዲ
ህም ፡ አለ ፡—እነሆ ፡ ደግሞ ፡ ሌላ ፡ ሕልምን ፡
አለምሁ ፤ እነሆ ፡ ፀሐይና ፡ ጨረቃ ፡ አሥራ ፡
፲ አንድ ፡ ከዋክብትም ፡ ሲሰግዱልኝ ፡ አየሁ ። ለአ
ባቱና ፡ ለወንድሞቹም ፡ ነገራቸው ፤ አባቱም ፡
ገሥጸው ፣ እንዲህም ፡ አለው ፡—ይህ ፡ ያለም
ኸው ፡ ሕልም ፡ ምንድር ፡ ነው ? በውኑ ፡ እኔና ፡
እናትህ ፡ ወንድሞችህም ፡ መጥተን ፡ በምድር ፡
፲፩ ላይ ፡ እንስገድልህ ፡ ይሆን ? ወንድሞቹም ፡ ቀኑ
በት ፡ አባቱ ፡ ግን ፡ ነገሩን ፡ ይጠብቀው ፡ ነበር ።
፲፪ ወንድሞቹ ፡ በሴኬም ፡ የአባታቸውን ፡ በጎች ፡
፲፫ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ሄዱ ። እስራኤልም ፡ ዮሴ
ፍን ፡—ወንድሞችህ ፡ በሴኬም ፡ በጎችን ፡ የሚ
ጠብቁ ፡ አይደሉምን ? ወደ ፡ እነርሱ ፡ እል
ክህ ፡ ዘንድ ፡ ና ፡ አለው ። እርሱም ፡—እነሆኝ ፡
፲፬ አለው ። እርሱም ፡—ሄደህ ፡ ወንድሞችህና ፡
በጎቹ ፡ ደኅና ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ እይ ፣ ወሬአቸው
ንም ፡ አምጣልኝ ፡ አለው ። እንዲህም ፡ ከኬብ
ሮን ፡ ቈላ ፡ ሰደደው ፣ ወደ ፡ ሴኬምም ፡ መጣ ።
፲፭ እነሆም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ሲቅበዘበዝ ፡ ሳለ ፡
አንድ ፡ ሰው ፡ አገኘው ፤ ሰውዮውም ፡—ምን ፡
፲፮ ትፈልጋለህ ? ብሎ ፡ ጠየቀው ። እርሱም ፡—
ወንድሞቼን ፡ እፈልጋለሁ ፤ በጎቹን ፡ የሚጠብ
ቁበት ፡ ወዴት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እባክህ ፡ ንገረኝ ፡
፲፯ አለ ። ሰውዮውም ፡— ከዚህ ፡ ተነሥተዋል ፤
ወደ ፡ ዶታይን ፡ እንሂድ ፡ ሲሉም ፡ ሰምቼአቸዋ
ለሁ ፡ አለው ። ዮሴፍም ፡ ወንድሞቹን ፡ ተከታ
ትሎ ፡ ሄደ ፣ በዶታይንም ፡ አገኛቸው ።
፲፰ እነርሱም ፡ በሩቅ ፡ ሳለ ፡ አዩት ፣ ወደ ፡ እነር
ሱም ፡ ገና ፡ ሳይቀርብ ፡ ይገድሉት ፡ ዘንድ ፡ በእ
፲፱ ርሱ ፡ ላይ ፡ ተማከሩ ። አንዱም ፡ ለአንዱ ፡ እን
ዲህ ፡ አለው ፡—ያ ፡ ባለ ፡ ሕልም ፡ ይኸው ፡ መጣ ።
፳ አሁንም ፡ ኑ ፣ እንግደለውና ፡ በአንድ ፡ ጕድ
ጓድ ፡ ውስጥ ፡ እንጣለው ፡—ክፉ ፡ አውሬም ፡
በላው ፡ እንላለን ፤ ከሕልሞቹም ፡ የሚሆነውን ፡
፳፩ እናያለን ። ሮቤልም ፡ ይህን ፡ ሰማ ፣ ከእጃቸ
ውም ፡ አዳነው ፣ እንዲህም ፡ አለ ፡— ሕይወቱን ፡
፳፪ አናጥፋ ። ሮቤል ፡—ደም ፡ አታፍስሱ ፤ በዚ
ህች ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ባለችው ፡ ጕድጓድ ፡
ጣሉት ፣ ነገር ፡ ግን ፡ እጃችሁን ፡ አትጣሉበት ፡
አላቸው ። እንዲህም ፡ ማለቱ ፡ ከእጃቸው ፡
ሊያድነውና ፡ ወደ ፡ አባቱ ፡ ሊመልሰው ፡ ነው ።
፳፫ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ዮሴፍም ፡ ወደ ፡ ወንድሞቹ ፡
በቀረበ ፡ ጊዜ ፡ የለበሳትን ፡ በብዙ ፡ ኅብር ፡ ያጌ
፳፬ ጠቺቱን ፡ ቀሚሱን ፡ ገፈፉት ፤ ወሰደውም ፡
ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ ጣሉት ፤ ጕድጓዱም ፡ ውኃ ፡
የሌለበት ፡ ደረቅ ፡ ነበረ ።
፳፭ እንጀራም ፡ ሊበሉ ፡ ተቀመጡ ፤ ዓይናቸው
ንም ፡ አንሥተው ፡ አዩ ፣ እነሆም ፡ የእስማኤላ
ውያን ፡ ነጋዶች ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ለመውረድ ፡ ከገ
ለዓድ ፡ መጡ ፤ ግመሎቻቸውም ፡ ሽቱና ፡ በለ
፳፮ ሳን ፡ ከርቤም ፡ ተጭነው ፡ ነበር ። ይሁዳም ፡
ወንድሞቹን ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— ወንድማች
ንን ፡ ገድለን ፡ ደሙን ፡ ብንሸሽግ ፡ ጥቅማችን ፡

፳፯ ምንድር ፡ ነው ? ኑ ፣ ለእስማኤላውያን ፡ እንሽ
ጠው ፣ እጃችንን ፡ ግን ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ አንጣል ፣
ወንድማችን ፡ ሥጋችንም ፡ ነውና ። ወንድሞ
፳፰ ቹም ፡ የእርሱን ፡ ነገር ፡ሰሙት ። የምድያም ፡
ነጋዶችም ፡ አለፉ ፤ እነርሱም ፡ ዮሴፍን ፡ አንሥ
ተው ፡ ከጕድጓድ ፡ አወጡት ፤ ለእስማኤላው
ያንም ፡ ዮሴፍን ፡ በሀያ ፡ ብር ፡ ሸጡት ፤ እነር
ሱም ፡ ዮሴፍን ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ወሰዱት ።
፳፱ ሮቤልም ፡ ወደ ፡ ጕድጓዱ ፡ ተመለሰ ፣ እነ
ሆም ፡ ዮሴፍ ፡ በጕድጓድ ፡ የለም ፤ ልብሱንም ፡
፴ ቀደደ ። ወደ ፡ ወንድሞቹም ፡ ተመልሶ ፡—
ብላቴናው ፡ የለም ፤ እንግዲህ ፡ እኔ ፡ ወዴት ፡
፴፩ እሄዳለሁ ? አለ ። የዮሴፍንም ፡ ቀሚስ ፡ ወሰዱ ፣
የፍየል ፡ አውራም ፡ አርደው ፡ ቀሚሱን ፡
፴፪ በደም ፡ ነከሩት ። ብዙ ፡ ኅብር ፡ ያለበትን ፡ ቀሚ
ሱንም ፡ ላኩ ፣ ወደ ፡ አባታቸውም ፡ አገቡት ፣
እንዲህም ፡ አሉት ፡— ይህንን ፡ አገኘን ፤ ይህ ፡
የልጅህ ፡ ልብስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ወይም ፡ እንዳል
፴፫ ሆነ ፡ እስኪ ፡ እየው ። እርሱም ፡ አውቆ ፡—
የልጄ ፡ ቀሚስ ፡ ነው ፤ ክፉ ፡ አውሬ ፡ በልቶ
ታል ፤ ዮሴፍ ፡ በእርግጥ ፡ ተበጫጭቋል ፡ አለ ።
፴፬ ያዕቆብም ፡ ልብሱን ፡ ቀደደ ፣ በወገቡም ፡ ማቅ ፡
፴፭ ታጥቆ ፡ ለልጁ ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ አለቀሰ ። ወንዶች ፡
ልጆቹና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቹም ፡ ሁሉ ፡ ሊያጽና
ኑት ፡ ተነሡ ፤ መጽናናትን ፡ እንቢ ፡ አለ ፣ እን
ዲህም ፡ አለ ፡— ወደ ፡ ልጄ ፡ ወደ ፡ ሙታን ፡
ስፍራ ፡ እያዘንሁ ፡ እወርዳለሁ ። አባቱም ፡ ስለ ፡
፴፮ እርሱ ፡ አለቀሰ ። እነዚያ ፡ የምድያም ፡ ሰዎች ፡
ግን ፡ ዮሴፍን ፡ በግብፅ ፡ ለፈርዖን ፡ ጃንደረባ ፡
ለዘበኞቹ ፡ አለቃ ፡ ለጲጥፋራ ፡ ሸጡት ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፰ ።

፩ በዚያም ፡ ወራት ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ ይሁዳ ፡
ከወንድሞቹ ፡ ተለይቶ ፡ ወረደ ፣ ስሙን ፡ ኤራስ ፡
ወደሚሉት ፡ ወደ ፡ ዓዶሎማዊውም ፡ ሰው ፡
፪ ገባ ። ከዚያም ፡ ይሁዳ ፡ የከነዓናዊውን ፡ የሴ
ዋን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ አየ ፤ ወሰዳትም ፣ ወደ ፡
፫ እርስዋም ፡ ገባ ። ፀነሰችም ፡ ወንድ ፡ ልጅ
ንም ፡ ወለደች ፤ ስሙንም ፡ ዔር ፡ ብላ ፡ ጠራ
፬ ችው ። ደግሞም ፡ ፀነሰች ፡ ወንድ ፡ ልጅንም ፡
ወለደች ፤ ስሙንም ፡ አውናን ፡ ብላ ፡ ጠራችው ።
፭ እንደ ፡ ገና ፡ ደግሞ ፡ ወንድ ፡ ልጅን ፡ ወለደች ፣
ስሙንም ፡ ሴሎም ፡ ብላ ፡ ጠራችው ፤ እርሱ
ንም ፡ በወለደች ፡ ጊዜ ፡ ክዚብ ፡ በሚባል ፡ አገር ፡
፮ ነበረች ። ይሁዳም ፡ ለበኵር ፡ ልጁ ፡ ለዔር ፡
፯ ትዕማር ፡ የምትባል ፡ ሚስት ፡ አጋባው ። የይ
ሁዳም ፡ የበኵር ፡ ልጅ ፡ ዔር ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ክፉ ፡ ነበረ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ቀሠፈው ።
፰ ይሁዳም ፡ አውናን ፡—ወደ ፡ ወንድምህ ፡ ሚስት ፡
ግባ ፣ አግባትም ፣ ለወንድምህም ፡ ዘርን ፡ አቁ
፱ ምለት ፡ አለው ። አውናንም ፡ ዘሩ ፡ ለእርሱ ፡
እንዳይሆን ፡ አወቀ ፤ ወደ ፡ ወንድሙ ፡ ሚስት ፡
በገባ ፡ ጊዜ ፡ ለወንድሙ ፡ ዘር ፡ እንዳይሰጥ ፡
፲ ዘሩን ፡ በምድር ፡ ያፈስሰው ፡ ነበር ። ይህም ፡

ሥራው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ክፉ ፡ ሆነ
፲፩ በት ÷ እርሱንም ፡ ደግሞ ፡ ቀሠፈው ። ይሁ
ዳም ፡ ምራቱን ፡ ትዕማርን ፡— ልጄ ፡ ሴሎም ፡
እስኪያድግ ፡ ድረስ ፡ በአባትሽ ፡ ቤት ፡ መበለት ፡
ሆነሽ ፡ ተቀመጪ ፡ አላት ፤ እርሱ ፡ ደግሞ ፡
እንደ ፡ ወንድሞቹ ፡ እንዳይሞት ፡ ብሎአልና ።
ትዕማርም ፡ ሄዳ ፡ በአባትዋ ፡ ቤት ፡ ተቀመጠች ።
፲፪ ከብዙ ፡ ዘመንም ፡ በኋላ ፡ የይሁዳ ፡ ሚስት ፡
የሴዋ ፡ ልጅ ፡ ሞተች ፤ ይሁዳም ፡ ተጽናና ÷
የበጎቹን ፡ ጠጕር ፡ ወደሚሸልቱት ፡ ሰዎችም ፡
ወደ ፡ ተምና ፡ ወጣ ÷ እርሱም ፡ ዓዶሎማዊው ፡
፲፫ ወዳጁም ፡ ኤራስ ። ለትዕማርም ፡— እነሆ ÷
አማትሽ ፡ ይሁዳ ፡ የበጎቹን ፡ ጠጕር ፡ ይሸልት ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ ተምና ፡ ይወጣል ፡ ብለው ፡ ነገሩ
፲፬ አት ። እርስዋም ፡ የመበለትነትዋን ፡ ልብስ ፡
አወለቀች ÷ መጐናጸፊያዋንም ፡ ወሰደች ÷ ተሸ
ፈነችም ÷ ወደ ፡ ተምናም ፡ በሚወስደው ፡ መን
ገድ ፡ ዳር ፡ በኤናይም ፡ ደጅ ፡ ተቀመጠች ፤
ሴሎም ፡ እንደ ፡ አደገ ፡ ሚስትም ፡ እንዳልሆን
፲፭ ችው ፡ አይታለችና ። ይሁዳም ፡ ባያት ፡ ጊዜ ፡
ጋለሞታን ፡ መሰለችው ፤ ፊትዋን ፡ ተሸፍና ፡
፲፮ ነበርና ። ወደ ፡ እርስዋም ፡ አዘነበለ ፡— እባ
ክሽ ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡ ልግባ ፡ አላት ፤ እርስዋ ፡
ምራቱ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ አላወቀም ፡ ነበርና ።
እርስዋም ፡— ወደ ፡ እኔ ፡ ብትገባ ፡ ምን ፡ ትሰጠ
፲፯ ኛለህ ? አለችው ። የፍየል ፡ ጠቦት ፡ ከመን
ጋዬ ፡ እሰድድልሻለሁ ፡ አላት ። እርስዋም ፡—
እስክትሰድድልኝ ፡ ድረስ ፡ መያዣ ፡ ትሰጠኛለ
፲፰ ህን ? አለችው ። እርሱም ፡— ምን ፡ መያዣ ፡
ልስጥሽ ? አላት ። እርስዋም ፡— ቀለበትህን ÷
አምባርህን ÷ በእጅህ ፡ ያለውን ፡ በትር ፡ አለች ።
እርሱም ፡ ሰጣትና ፡ ከእርስዋ ፡ ደረሰ ÷ እርስ
፲፱ ዋም ፡ ፀነሰችለት ። እርስዋም ፡ ተነሥታ ፡
ሄደች ÷ መጐናጸፊያዋንም ፡ አውልቃ ፡ የመበ
፳ ለትነትዋን ፡ ልብስ ፡ ለበሰች ። ይሁዳም ፡ መያ
ዣውን ፡ ከሴቲቱ ፡ እጅ ፡ ይቀበል ፡ ዘንድ ፡ በወ
ዳጁ ፡ በዓዶሎማዊው ፡ እጅ ፡ የፍየሉን ፡ ጠቦት ፡
፳፩ ላከላት ፤ እርስዋንም ፡ አላገኛትም ። እርሱም ፡
የአገሩን ፡ ሰዎች ፡— በኤናይም ፡ በመንገድ ፡
ዳር ፡ ተቀምጣ ፡ የነበረች ፡ ጋለሞታ ፡ ወዴት ፡
ናት ? ብሎ ፡ ጠየቃቸው ። እነርሱም ፡— በዚህ ፡
፳፪ ጋለሞታ ፡ አልነበረችም ፡ አሉት ። ወደ ፡ ይሁ
ዳም ፡ ተመልሶ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— አላገኘኋ
ትም ፤ የአገሩም ፡ ሰዎች ፡ ደግሞ ፡— ከዚህ ፡
፳፫ ጋለሞታ ፡ አልነበረችም ፡ አሉኝ ። ይሁዳም ፡—
እኛ ፡ መዘበቻ ፡ እንዳንሆን ፡ ትውሰደው ፤ እነሆ ፡
የፍየሉን ፡ ጠቦት ፡ ሰደድሁላት ÷ አንተም ፡ አላ
ገኘሃትም ፡ አለ ።
፳፬ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ከሦስት ፡ ወር ፡ በኋላ ፡ ለይ
ሁዳ ፡— ምራትህ ፡ ትዕማር ፡ ሴሰነች ፤ ደግሞም ፡
በዝሙት ፡ እነሆ ፡ ፀነሰች ፡ ብለው ፡ ነገሩት ።
ይሁዳም ፡— አውጡአትና ፡ በእሳት ፡ ትቃጠል ፡
፳፭ አለ ። እርስዋም ፡ ባወጡአት ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡
አማትዋ ፡ እንዲህ ፡ ብላ ፡ ላከች ፡— ለዚህ ፡ ለባለ ፡
ገንዘብ ፡ ነው ፡ የፀነስሁት ፤ ተመልከት ፤ ይህ ፡
ቀለበት ÷ ይህ ፡ አምባር ÷ ይህ ፡ በትር ፡ የማን ፡
፳፮ ነው ? ይሁዳም ፡ አወቀ ፡— ከእኔ ፡ ይልቅ ፡ እር
ስዋ ፡ እውነተኛ ፡ ሆነች ፤ ልጄን ፡ ሴሎምን ፡
አልሰጠኋትምና ፡ አለ ። ደግሞም ፡ አላወቃ
፳፯ ትም ። በመውለጃዋም ፡ ጊዜ ፡ እነሆ ፡ መንታ ፡
፳፰ ልጆች ፡ በሆድዋ ፡ ነበሩ ። ስትወልድም ፡ አንዱ ፡
እጁን ፡ አወጣ ፤ አዋላጂቱም ፡ ቀይ ፡ ፈትል ፡
ወስዳ ፡ በእጁ ፡ አሰረች ፡— ይህ ፡ መጀመሪያ ፡
፳፱ ይወጣል ፡ አለች ። እንዲህም ፡ ሆነ ፤ እጁን ፡
በመለሰ ፡ ጊዜ ፡ እነሆ ፡ ወንድሙ ፡ ወጣ ፤ እር
ስዋም ፡— ለምን ፡ ጥሰህ ፡ ወጣህ ? አለች ፤
፴ ስሙንም ፡ ፋሬስ ፡ ብላ ፡ ጠራችው ። ከእርሱም ፡
በኋላ ፡ ቀይ ፡ ፈትል ፡ በእጁ ፡ ያለበት ፡ ወንድሙ ፡
ወጣ ፤ ስሙም ፡ ዛራ ፡ ተባለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፱ ።

፩ ዮሴፍ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ወረደ ፤ የፈርዖን ፡
ጃንደረባ ፡ የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ የሚሆን ፡ የግ
ብፅ ፡ ሰው ፡ ጲጥፋራ ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ከወረዱት ፡
፪ ከእስማኤላውያን ፡ እጅ ፡ ገዛው ። እግዚአብ
ሔር ፡ ከዮሴፍ ፡ ጋር ፡ ነበረ ÷ ሥራውም ፡ የተ
ከናወነለት ፡ ሰው ፡ ሆነ ፤ በግብፃዊው ፡ ጌታ
፫ ውም ፡ ቤት ፡ ነበረ ። ጌታውም ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ እንዳለ ÷ እርሱ ፡ የሚ
ሠራውንም ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእጁ ፡ እን
፬ ዲያከናውንለት ፡ አየ ። ዮሴፍም ፡ በጌታው ፡
ፊት ፡ ሞገስን ፡ አገኘ ÷ እርሱንም ፡ ያገለግለው ፡
ነበር ፤ በቤቱም ፡ ላይ ፡ ሾመው ÷ ያለውንም ፡
፭ ሁሉ ፡ በእጁ ፡ ሰጠው ። እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በቤቱ ፡
ባለውም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከሾመው ፡ በኋላ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ የግብፃዊውን ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ ዮሴፍ ፡
ባረከው ፤ የእግዚአብሔር ፡ በረከት ፡ በውጪም ፡
፮ በግቢም ፡ ባለው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሆነ ። ያለውንም ፡
ሁሉ ፡ ለዮሴፍ ፡ አስረከበ ፤ ከሚበላውም ፡ እን
ጀራ ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ የሚያውቀው ፡ አልነበ
ረም ። የዮሴፍም ፡ ፊቱ ፡ መልከ ፡ መልካምና ፡
ውብ ፡ ነበረ ።
፯ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ የጌታው ፡
ሚስት ፡ በዮሴፍ ፡ ላይ ፡ ዓይንዋን ፡ ጣለች ፡—
፰ ከእኔም ፡ ጋር ፡ ተኛ ፡ አለችው ። እርሱም ፡
እንቢ ፡ አለ ÷ ለጌታውም ፡ ሚስት ፡ እንዲህ ፡
አላት ፡— እነሆ ፡ ጌታዬ ፡ በቤቱ ፡ ያለውን ፡
ምንም ፡ ምን ፡ የሚያውቀው ፡ የለም ÷ ያለው
፱ ንም ፡ ሁሉ ፡ ለእኔ ፡ አስረከበኛል ፤ ለዚህ ፡ ቤት ፡
ከእኔ ፡ የሚበልጥ ፡ ሰው ፡ የለም ፤ ሚስቱ ፡ ስለ ፡
ሆንሽ ፡ ከአንቺም ፡ በቀር ፡ ያልሰጠኝ ፡ ነገር ፡
የለም ፤ እንዴት ፡ ይህን ፡ ትልቅ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡
አደርጋለሁ ? በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንዴት ፡
፲ ኃጢአትን ፡ እሠራለሁ ? ይህንም ፡ ነገር ፡ በየ
ዕለቱ ፡ ለዮሴፍ ፡ ትነግረው ፡ ነበር ፤ እርሱም ፡
ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ ይተኛ ፡ ዘንድ ፡ ከእርስዋም ፡
፲፩ ጋር ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ አልሰማትም ። እንዲህም ፡
ሆነ ፤ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሥራውን ፡ እንዲሠራ ፤

ወደ ፡ ቤቱ ፡ ገባ ፤ በቤትም ፡ ውስጥ ፡ ከቤት ፡
፲፪ ፤ ሰዎች ፡ ማንም ፡ አልነበረም ። ከእኔ ፡ ጋር ፡ ተኛ ፡
ስትል ፡ ልብሱን ፡ ተጠማጥማ ፡ ያዘች ፤ እርሱም ፡
ልብሱን ፡ በእጅዋ ፡ ትቶላት ፡ ሸሸ ፡ ወደ ፡ ው
፲፫ ፤ ጭም ፡ ወጣ ። እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ልብሱን ፡ ትቶ ፡
፲፬ ፤ ወደ ፡ ውጭ ፡ እንደ ፡ ሸሸ ፡ ባየች ፡ ጊዜ ÷ የቤት
ዋን ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ጠርታ ፡ እንዲህ ፡
ብላ ፡ ነገረቻቸው ፡— እዩ ፤ ዕብራዊው ፡ ሰው ፡
በእኛ ፡ እንዲሣለቅ ፡ አግብቶብናል ፤ እርሱ ፡
ከእኔ ፡ ጋር ፡ ሊተኛ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ገባ ÷ እኔም ፡
፲፭ ፤ ድምፄን ፡ ከፍ ፡ አድርጌ ፡ ጮኽሁ ፤ ድምፄንም ፡
ከፍ ፡ አድርጌ ፡ እንደ ፡ ጮኽሁ ፡ ቢሰማ ÷ ልብ
ሱን ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ጥሎ ፡ ሸሸ ፡ ወደ ፡ ውጭም ፡
፲፮ ፤ ወጣ ። ጌታው ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ እስኪገባ ፡ ድረ
ስም ፡ ልብሱን ፡ ከእርስዋ ፡ ዘንድ ፡ አኖረች ።
፲፯ ፤ ይህንም ፡ ነገር ፡ እንዲህ ፡ ብላ ፡ ነገረችው ፡—
ያገባህልን ፡ ዕብራዊው ፡ ባሪያ ፡ ሊሣለቅብኝ ፡ ወደ ፡
፲፰ ፤ እኔ ፡ ገባ ፤ እኔም ፡ ድምፄን ፡ ከፍ ፡ አድርጌ ፡ ስጮኽ ፡
ልብሱን ፡ በእጄ ፡ ተወና ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ሸሸ ።
፲፱ ፤ ጌታውም ፡— ባሪያህ ፡ እንዲህ ፡ አደረገኝ ፡
ብላ ፡ የነገረችውን ፡ የሚስቱን ፡ ቃል ፡ በሰማ ፡
፳ ፤ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ። የዮሴፍም ፡ ጌታ ፡ ወሰ
ደው ÷ የንጉሡ ፡ እስረኞችም ፡ ወደሚታሰሩ
በት ፡ ስፍራ ፡ ወደ ፡ ግዞት ፡ ቤት ፡ አገባው ፤ ከዚ
፳፩ ፤ ያም ፡ በግዞት ፡ ነበረ ። እግዚአብሔርም ፡ ከዮ
ሴፍ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፡ ምሕረትንም ፡ አበዛለት ÷
በግዞት ፡ ቤቱም ፡ አለቃ ፡ ፊት ፡ ሞገስን ፡ ሰጠው ።
፳፪ ፤ የግዞት ፡ ቤቱም ፡ አለቃ ፡ በግዞት ፡ ያሉትን ፡
እስረኞች ፡ ሁሉ ፡ በዮሴፍ ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣ
ቸው ፤ በዚያም ፡ የሚደረገው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እርሱ ፡
፳፫ ፤ የሚያደርገው ፡ ነበረ ። የግዞት ፡ ቤቱም ፡ አለቃ ፡
በእጁ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ ከቶ ፡ አላሰበም ÷ እግዚ
አብሔር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረና ፤ የሚያደርገው
ንም ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያቀናለት ፡ ነበር ።

ምዕራፍ ፡ ፵ ።

፩ ፤ ከዚህ ፡ ነገር ፡ በኋላም ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ የግ
ብፅ ፡ ንጉሥ ፡ የጠጅ ፡ አሳላፊና ፡ የእንጀራ ፡
አበዛ ፡ ጌታቸውን ፡ የግብፅ ፡ ንጉሥን ፡ በደሉ ።
፪ ፤ ፈርዖንም ፡ በሁለቱ ፡ ሹማምቱ ፡ በጠጅ ፡ አሳላ
ፊዎቹ ፡ አለቃና ፡ በእንጀራ ፡ አበዛዎቹ ፡ አለቃ ፡
፫ ፤ ላይ ፡ ተቈጣ ፤ ዮሴፍ ፡ ታስሮ ፡ በነበረበትም ፡
በግዞት ፡ ስፍራ ፡ በዘበኞቹ ፡ አለቃ ፡ ቤት ፡ አስ
፬ ፤ ጠበቃቸው ። የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ ለዮሴፍ ፡
አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ÷ እርሱም ፡ ያገለግላቸው ፡
ነበር ፤ በግዞት ፡ ቤትም ፡ አያሌ ፡ ቀን ፡ ተቀመጡ ።
፭ ፤ በግዞት ፡ ቤት ፡ የነበሩት ፡ የግብፅ ፡ ንጉሥ ፡
ጠጅ ፡ አሳላፊና ፡ እንጀራ ፡ አበዛ ፡ ሁለቱም ፡
በአንዲት ፡ ሌሊት ፡ እንደ ፡ ሕልሙ ፡ ትርጓሜ ፡
፮ ፤ እየራሳቸው ፡ ሕልምን ፡ አለሙ ። ዮሴፍም ፡
ማልዶ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ገባ ÷ እነሆም ፡ አዝነው ፡
፯ ፤ አያቸው ። በጌታው ፡ ቤት ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
በግዞት ፡ የነበሩትንም ፡ የፈርዖንን ፡ ሹማምት ፡
እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ጠየቃቸው ፡— እናንተ ፡ ዛሬ ፡
፰ ፤ ስለ ፡ ምን ፡ አዝናችኋል ? እነርሱም ፡— ሕል
ምን ፡ አልመን ፡ የሚተረጕምልን ፡ አጣን ፡
አሉት ። ዮሴፍም ፡ አላቸው ፡— ሕልምን ፡ የሚ
ተረጕም ፡ እግዚአብሔር ፡ የሰጠው ፡ አይደለ
ምን ? እስቲ ፡ ንገሩኝ ።
፱ ፤ የጠጅ ፡ አሳላፊዎች ፡ አለቃም ፡ ለዮሴፍ ፡
ሕልሙን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ነገረው ፡— በሕልሜ ፡
፲ ፤ የወይን ፡ ዛፍ ፡ በፊቴ ፡ ሆና ፡ አየሁ ÷ በዛፊቱም ፡
ሦስት ፡ አረግ ፡ አለባት ፤ እርስዋም ፡ ቅጠልና ፡
አበባ ፡ አወጣች ÷ ዘለላም ፡ አንጠለጠለች ÷
፲፩ ፤ የዘለላዋም ፡ ፍሬ ፡ በሰለ ፤ የፈርዖንም ፡ ጽዋ ፡
በእጄ ፡ ነበረ ፤ ፍሬውንም ፡ ወስጄ ፡ በፈርዖን ፡
ጽዋ ፡ ጨመቅሁት ÷ ጽዋውንም ፡ ለፈርዖን ፡
፲፪ ፤ በእጁ ፡ ሰጠሁት ። ዮሴፍም ፡ አለው ፡— የዚህ ፡
ትርጓሜው ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ሦስቱ ፡ አረግ ፡ ሦስት ፡
፲፫ ፤ ቀን ፡ ነው ፤ እስከ ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ፈር
ዖን ፡ ራስህን ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ÷ ወደ ፡ ቀደመው ፡
ሹመትህም ፡ ይመልስሃል ፤ ጠጅ ፡ አሳላፊ ፡ በነ
በርህበት ፡ ጊዜ ፡ ስታደርግ ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡
እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ሥርዓትም ፡ የፈርዖንን ፡ ጽዋ ፡
፲፬ ፤ በእጁ ፡ ትሰጣለህ ። ነገር ፡ ግን ፡ በጎ ፡ ነገር ፡
በተደረገልህ ፡ ጊዜ ፡ እኔን ፡ አስበኝ ÷ ምሕረት
ንም ፡ አድርግልኝ ÷ የእኔንም ፡ ነገር ፡ ለፈርዖን ፡
፲፭ ፤ ንግረህ ፡ ከዚህ ፡ ቤት ፡ አውጣኝ ፤ እኔን ፡ ከዕብ
ራውያን ፡ አገር ፡ ሰርቀው ፡ አምጥተውኛልና ፤
ከዚህም ፡ ደግሞ ፡ በግዞት ፡ ያኖሩኝ ፡ ዘንድ ፡
ምንም ፡ አላደረግሁም ።
፲፮ ፤ የእንጀራ ፡ አበዛዎቹ ፡ አለቃም ፡ ሕልሙን ፡
በመልካም ፡ እንደ ፡ ተረጐመ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ዮሴ
ፍን ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— እኔም ፡ ደግሞ ፡ ሕልም ፡
አይቼ ፡ ነበር ÷ እነሆም ፡ ሦስት ፡ መሶብ ፡ ነጭ ፡
፲፯ ፤ እንጀራ ፡ በራሴ ፡ ላይ ፡ ነበረ ፤ በላይኛውም ፡
መሶብ ፡ ፈርዖን ፡ ከሚበላው ፡ ከጋጋሪዎች ፡
ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ነበረበት ፤ ወፎችም ፡ በራሴ ፡ ላይ ፡
፲፰ ፤ ከመሶቡ ፡ ይበሉ ፡ ነበር ። ዮሴፍም ፡ መልሶ ፡
እንዲህ ፡ አለው ፡— የዚህ ፡ ትርጓሜው ፡ ይህ ፡
ነው ፤ ሦስቱ ፡ መሶብ ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ነው ፤
፲፱ ፤ እስከ ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ፈርዖን ፡ ራስህን ፡
ከፍ ፡ ያደርጋል ÷ በእንጨትም ፡ ላይ ፡ ይሰቅል
ሃል ፤ ወፎችም ፡ ሥጋህን ፡ ይበሉታል ። በሦ
፳ ፤ ስተኛውም ፡ ቀን ፡ ፈርዖን ፡ የተወለደበት ፡ ቀን ፡
ነበረ ÷ ለሠራዊቱም ፡ ሁሉ ፡ ግብር ፡ አደረገ ፤
የጠጅ ፡ አሳላፊዎቹን ፡ አለቃና ፡ የእንጀራ ፡ አበ
ዛዎቹን ፡ አለቃ ፡ በአሽከሮቹ ፡ መካከል ፡ ከፍ ፡
፳፩ ፤ አደረገ ። የጠጅ ፡ አሳላፊዎቹንም ፡ አለቃ ፡
ወደ ፡ ስፍራው ፡ መለሰው ÷ ጽዋውንም ፡ በፈ
፳፪ ፤ ርዖን ፡ እጅ ፡ ሰጠ ፤ የእንጀራ ፡ አበዛዎቹንም ፡
አለቃ ፡ ሰቀለው ÷ ዮሴፍ ፡ እንደ ፡ ተረጐመላ
፳፫ ፤ ቸው ። የጠጅ ፡ አሳላፊዎች ፡ አለቃ ፡ ግን ፡
ዮሴፍን ፡ አላሰበውም ÷ ረሳው ፡ እንጂ ።

ምዕራፍ ፡ ፵፩ ።

፩ ፤ ከሁለት ፡ ዓመት ፡ በኋላም ፡ ፈርዖን ፡ ሕል
ምን ፡ አየ ፤ እነሆም ÷ በወንዙ ፡ ዳር ፡ ቆሞ ፡

፪ ነበር ። እነሆም ፥ መልካቸው ፡ ያማረ ፡ ሥጋቸ
ውም ፡ የወፈረ ፡ ሰባት ፡ ላሞች ፡ ከወንዙ ፡ ወጡ ፥
በውኃውም ፡ ዳር ፡ በመስኩ ፡ ይሰማሩ ፡ ነበር ።
፫ ከእነርሱም ፡ በኋላ ፡ እነሆ ፡ መልካቸው ፡ የከፋ ፡
ሥጋቸውም ፡ የከሳ ፡ ሌሎች ፡ ሰባት ፡ ላሞች ፡
ከወንዝ ፡ ወጡ ፥ በእነዚያም ፡ ላሞች ፡ አጠገብ ፡
፬ በወንዙ ፡ ዳር ፡ ይቆሙ ፡ ነበር ። መልካቸው ፡
የከፋ ፡ ሥጋቸውም ፡ የከሳ ፡ እነዚያም ፡ ላሞች ፡
መልካቸው ፡ ያማረውን ፡ ሥጋቸው ፡ የወፈረ
ውን ፡ ሰባቱን ፡ ላሞች ፡ ዋጡአቸው ። ፈርዖ
፭ ንም ፡ ነቃ ። ደግሞም ፡ ተኛ ፡ ሁለተኛም ፡ ሕል
ምን ፡ አየ ፤ እነሆም ፡ በአንድ ፡ አገዳ ፡ ላይ ፡ የነ
በሩ ፡ ያማሩና ፡ መልካም ፡ የሆኑ ፡ ሰባት ፡ እሸ
፮ ቶች ፡ ወጡ ፤ እነሆም ፡ ከእነርሱ ፡ በኋላ ፡
የሰለቱና ፡ በምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ የተመቱ ፡ ሰባት ፡
፯ እሸቶች ፡ ወጡ ፤ የሰለቱትም ፡ እሸቶች ፡ ሰባ
ቱን ፡ ያማሩና ፡ የዳበሩ ፡ እሸቶች ፡ ዋጡአቸው ።
፰ ፈርዖንም ፡ ነቃ ፥ እነሆም ፡ ሕልም ፡ ነበረ ። በነ
ጋም ፡ ጊዜ ፡ ነፍሱ ፡ ታወከችበት ፤ ወደ ፡ ሕልም ፡
ተርጓሚዎች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ጠቢባንም ፡
ሁሉ ፡ ልከ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ጠራቸው ፤ ፈርዖ
ንም ፡ ሕልሙን ፡ ነገራቸው ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ከእ
ነርሱ ፡ ለፈርዖን ፡ የሚተረጕም ፡ አልተገኘም ።
፱ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የጠጅ ፡ አሳላፊዎቹ ፡ አለቃ ፡
እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ለፈርዖን ፡ ተናገረ ፡— እኔ ፡ ኃጢ
፲ አቴን ፡ ዛሬ ፡ አስባለሁ ፤ ፈርዖን ፡ በባሪያዎቹ ፡
ላይ ፡ ተቈጣ ፥ እኔንም ፡ የእንጀራ ፡ አበዛዎቹንም ፡
አለቃ ፡ በግዞት ፡ ስፍራ ፡ በዘበኞች ፡ አለቃ ፡ ቤት ፡
፲፩ አኖረን ፤ እኛም ፡ በአንዲት ፡ ሌሊት ፡ ሕልምን ፡
አለምን ፥ እኔና ፡ እርሱ ፤ እያንዳንዳችን ፡ እንደ ፡
፲፪ ሕልማችን ፡ ትርጓሜ ፡ አለምን ። በዚያም ፡ የዘ
በኞቹ ፡ አለቃ ፡ ባሪያ ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ ዕብራዊ ፡
ጐልማሳ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፤ ለእርሱም ፡ ነገር
ነው ፥ ሕልማችንንም ፡ ተረጐመልን ፤ ለእያንዳ
፲፫ ንዱም ፡ እንደ ፡ ሕልሙ ፡ ተረጐመልን ። እንዲ
ህም ፡ ሆነ ፤ እንደ ፡ ተረጐመልን ፡ እንደዚያው ፡
ሆነ ፤ እኔ ፡ ወደ ፡ ሹመቴ ፡ ተመለስሁ ፥ እር
ሱም ፡ ተሰቀለ ።
፲፬ ፈርዖንም ፡ ልከ ፡ ዮሴፍን ፡ አስጠራ ፥ ከግ
ዞት ፡ ቤትም ፡ አስቸኰሉት ፤ እርሱም ፡ ተላጨ ፥
ልብሱንም ፡ ለወጠ ፥ ወደ ፡ ፈርዖንም ፡ ገባ ።
፲፭ ፈርዖንም ፡ ዮሴፍን ፡ አለው ፡— ሕልምን ፡
አየሁ ፥ የሚተረጕመውም ፡ አልተገኘም ፤
ሕልምን ፡ እንደ ፡ ሰማህ ፥ እንደ ፡ ተረጐም
፲፮ ህም ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ ሰማሁ ። ዮሴፍም ፡ ለፈር
ዖን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ መለሰ ፡— ይህ ፡ በእኔ ፡
አይደለም ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ለፈርዖን ፡
፲፯ በደኅንነት ፡ ይመልስለታል ። ፈርዖንም ፡ ለዮ
ሴፍ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— እነሆ ፥ በሕልሜ ፡
፲፰ በወንዝ ፡ ዳር ፡ ቆሜ ፡ ነበር ፤ እነሆም ፥
ሥጋቸው ፡ የወፈረ ፡ መልካቸውም ፡ ያማረ ፡
ሰባት ፡ ላሞች ፡ ወጡ ፥ በመስኩም ፡ ይሰማሩ ፡
፲፱ ነበር ፤ ከእነርሱም ፡ በኋላ ፡ እነሆ ፡ የደከሙ ፡
መልካቸውም ፡ እጅግ ፡ የከፋ ፡ ሥጋቸውም ፡
የከሳ ፡ ሌሎች ፡ ሰባት ፡ ላሞች ፡ ወጡ ፤ በግብ
ፅም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ እነርሱ ፡ መልከ ፡
፳ ክፉ ፡ ከቶ ፡ አላየሁም ፤ የከሱትና ፡ መልከ ፡ ክፉ
ዎቹ ፡ ላሞች ፡ የመጀመሪያዎቹን ፡ ወፍራሞቹን ፡
፳፩ ሰባት ፡ ላሞች ፡ ዋጡአቸው ፥ በሆዳቸውም ፡
ተዋጡ ፤ በሆዳቸውም ፡ እንደ ፡ ተዋጡ ፡ አልታ
ወቀም ፥ መልካቸውም ፡ በመጀመሪያ ፡ እንደ ፡
፳፪ ነበረው ፡ የከፋ ፡ ነበረ ። ነቃሁም ። በሕልሜም ፡
እነሆ ፡ የዳበሩና ፡ መልካም ፡ የሆኑ ፡ ሰባት ፡ እሸ
፳፫ ቶች ፡ በአንድ ፡ አገዳ ፡ ሲወጡ ፡ አየሁ ፤ ከእነር
ሱም ፡ በኋላ ፡ እነሆ ፡ የደረቁና ፡ የሰለቱ ፡ በም
ሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ የተመቱ ፡ ሰባት ፡ እሸቶች ፡ ወጡ ፤
፳፬ የሰለቱት ፡ እሸቶች ፡ ያማሩትን ፡ ሰባቱን ፡ እሸ
ቶች ፡ ዋጡአቸው ። ለሕልም ፡ ተርጓሚዎችም ፡
ሕልሜን ፡ ነገርሁ ፡ የሚተረጕምልኝም ፡ አጣሁ ።
፳፭ ዮሴፍም ፡ ፈርዖንን ፡ አለው ፡— የፈርዖን ፡
ሕልሙ ፡ አንድ ፡ ነው ፤ እግዚአብሔር ፡ ሊያ
፳፮ ደርገው ፡ ያለውን ፡ ለፈርዖን ፡ ነግሮታል ። ሰባቱ ፡
መልካካሞች ፡ ላሞች ፡ ሰባት ፡ ዓመታት ፡ ናቸው ፥
ሰባቱም ፡ መልካካሞች ፡ እሸቶች ፡ ሰባት ፡ ዓመ
፳፯ ታት ፡ ናቸው ፤ ሕልሙ ፡ አንድ ፡ ነው ። ከእ
ነርሱም ፡ በኋላ ፡ የወጡት ፡ የከሱትና ፡ መልከ ፡
ክፉዎቹ ፡ ሰባት ፡ ላሞች ፡ ሰባት ፡ ዓመታት ፡
ናቸው ፥ የሰለቱትና ፡ የምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ የመ
ታቸው ፡ ሰባቱም ፡ እሸቶች ፡ እነርሱ ፡ ራብ ፡ የሚ
፳፰ ሆንባቸው ፡ ሰባት ፡ ዓመታት ፡ ናቸው ። ለፈር
ዖን ፡ የነገርሁት ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ እግዚአብ
ሔር ፡ ሊያደርገው ፡ ያለውን ፡ ለፈርዖን ፡ አሳየው ።
፳፱ እነሆ ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ እጅግ ፡ ጥጋብ ፡
የሚሆንባቸው ፡ ሰባት ፡ ዓመታት ፡ ይመጣሉ ፤
፴ ደግሞ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የሰባት ፡ ዓመት ፡ ራብ ፡
ይመጣል ፥ በግብፅ ፡ አገር ፡ የነበረውም ፡ ጥጋብ ፡
ሁሉ ፡ ይረሳል ፤ ራብም ፡ ምድርን ፡ በጣም ፡
፴፩ ያጠፋል ፤ በኋላ ፡ ከሚሆነው ፡ ከዚያ ፡ ራብ ፡
የተነሣም ፡ በምድር ፡ የሆነው ፡ ጥጋብ ፡ አይታ
፴፪ ወቅም ፥ እጅግ ፡ ጽኑ ፡ ይሆናልና ። ሕልሙም ፡
ለፈርዖን ፡ ደጋግሞ ፡ መታየቱ ፡ ነገሩ ፡ ከእግ
ዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተቈረጠ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡
ነው ፥ እግዚአብሔርም ፡ ፈጥኖ ፡ ያደርገዋል ።
፴፫ አሁንም ፡ ፈርዖን ፡ ብልህና ፡ አዋቂ ፡ ሰውን ፡
ይፈልግ ፥ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ላይም ፡ ይሹ
፴፬ መው ። ፈርዖን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ሹማምትን ፡
ይሹም ፤ በሰባቱም ፡ የጥጋብ ፡ ዓመታት ፡ ከሚ
ገኘው ፡ ፍሬ ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ከአም
፴፭ ስት ፡ እጅ ፡ አንደኛውን ፡ ይውሰድ ። የሚመ
ጡትን ፡ የመልካሞቹን ፡ ዓመታት ፡ እህላቸውን ፡
ያከማቹ ፤ ስንዴውንም ፡ ከፈርዖን ፡ እጅ ፡ በታች ፡
ያኑሩ ፥ እህሎችም ፡ በከተሞች ፡ ይጠበቁ ።
፴፮ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ስለሚሆነው ፡ ስለ ፡ ሰባቱ ፡
ዓመታት ፡ ራብ ፡ እህሉ ፡ ተጠብቆ ፡ ይኑር ፥ ምድ
ሪቱም ፡ በራብ ፡ አትጠፋም ።
፴፯ ነገሩም ፡ በፈርዖንና ፡ በሎሌዎቹ ፡ ፊት ፡ መል
፴፰ ካም ፡ ሆነ ፤ ፈርዖንም ፡ ሎሌዎቹን ፡ እንዲህ ፡
አላቸው ፡— በውኑ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡

ያለበትን ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ እናገኛለንን? ፴፱ ፈርዖንም ፡ ዮሴፍን ፡ አለው ፡— እንደ ፡ አንተ ፡ ያለ ፡ ብልህ ፡ አዋቂም ፡ ሰው ፡ የለም ÷ እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ገልጦልሃልና ። ፵ አንተ ፡ በቤቴ ፡ ላይ ፡ ተሾም ፡ ሕዝቤም ፡ ሁሉ ፡ ለቃልህ ፡ ይታዘዝ ፤ እኔ ፡ በዙፋኔ ፡ ብቻ ፡ ከአንተ ፡ እበልጣለሁ ። ፵፩ ፈርዖንም ፡ ዮሴፍን ፡— በግብፅ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሾምሁህ ፡ አለው ። ፵፪ ፈርዖን ፡ ቀለበቱን ፡ ከእጁ ፡ አወለቀ ፡ በዮሴፍ ፡ እጅም ፡ አደረገው ÷ ነጭ ፡ የተልባ ፡ እግር ፡ ልብስንም ፡ አለበሰው ÷ በአንገቱም ፡ የወርቅ ፡ ዝርግፍን ፡ አደረገለት ፤ ፵፫ የእርሱም ፡ በምትሆን ፡ በሁለተኛይቱ ፡ ሰረገላ ፡ አስቀመጠው ÷ አዋጅ ፡ ነጋሪም ፡— ስገዱ ፡ እያለ ፡ በፊት ፡ በፊቱ ፡ ይጮኽ ፡ ነበር ፤ እርሱም ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ተሾመ ። ፵፬ ፈርዖንም ፡ ዮሴፍን ፡ አለው ፡— እኔ ፡ ፈርዖን ፡ ነኝ ፤ በግብፅ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ያለ ፡ አንተ ፡ ማንም ፡ እጁንም ፡ እግሩንም ፡ አያንሣ ። ፵፭ ፈርዖንም ፡ የዮሴፍን ፡ ስም ፡ ጻፍናት ፡ ፐዕናህ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ፤ የሄልዮቱ ፡ ከተማ ፡ ካህን ፡ የጶጥፌራ ፡ ልጅ ፡ የምትሆን ፡ አስናትን ፡ አጋባው ። ዮሴፍም ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ወጣ ።

፵፮ ዮሴፍም ፡ በግብፅ ፡ ንጉሥ ፡ በፈርዖን ፡ ፊት ፡ በቆመ ፡ ጊዜ ፡ ዕድሜው ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ነበረ ። ዮሴፍም ፡ ከፈርዖን ፡ ፊት ፡ ወጣ ÷ የግብፅ ፡ ምድርንም ፡ ሁሉ ፡ ዞረ ። ፵፯ በሰባቱም ፡ በጥጋብ ፡ ዓመታት ፡ የምድሪቱ ፡ ፍሬ ፡ ክምር ፡ ሆነ ። ፵፰ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ያለውን ፡ የሰባቱን ፡ ዓመት ፡ እህል ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰበ ÷ እህልንም ፡ በከተሞቹ ፡ አደለበ ፤ በየከተማይቱ ፡ ዙሪያ ፡ ያለውን ፡ የእርሻውን ፡ እህል ፡ ሁሉ ፡ በዚያው ፡ ከተተ ። ፵፱ ዮሴፍም ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ አሸዋ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ የሆነ ፡ ስንዴን ፡ አከማቸ ÷ መስፈርን ፡ እስኪተው ፡ ድረስ ፤ ሊሰፈር ፡ አልተቻለምና ።

፶ ለዮሴፍም ፡ የሄልዮቱ ፡ ከተማ ፡ ካህን ፡ የጶጥፌራ ፡ ልጅ ፡ አስናት ፡ የወለደችለት ፡ ሁለት ፡ ልጆች ፡ የራብ ፡ ዘመን ፡ ገና ፡ ሳይመጣ ፡ ተወለዱለት ። ፶፩ ዮሴፍም ፡ የበኵር ፡ ልጁን ፡ ስም ፡ ምናሴ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ÷ እንዲህ ፡ ሲል ፡— እግዚአብሔር ፡ መከራዬን ፡ ሁሉ ፡ የአባቴንም ፡ ቤት ፡ አስረሳኝ ፤ ፶፪ የሁለተኛውንም ፡ ስም ፡ ኤፍሬም ፡ ብሎ ፡ ጠራው ÷ እንዲህ ፡ ሲል ፡— እግዚአብሔር ፡ በመከራዬ ፡ አገር ፡ አፈራኝ ።

፶፫ በግብፅ ፡ ምድር ፡ የነበረውም ፡ የሰባቱ ፡ ዓመት ፡ ፶፬ ጥጋብ ፡ አለፈ ÷ ዮሴፍም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ የሰባቱ ፡ ዓመት ፡ ራብ ፡ ጀመረ ። በየአገሩም ፡ ሁሉ ፡ ራብ ፡ ሆነ ፤ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ እህል ፡ ፶፭ ነበረ ። የግብፅ ፡ ምድርም ፡ ሁሉ ፡ ተራበ ÷ ሕዝቡም ፡ ስለ ፡ እህል ፡ ወደ ፡ ፈርዖን ፡ ጮኸ ፤ ፈርዖንም ፡ የግብፅ ፡ ሰዎችን ፡ ሁሉ ፡— ወደ ፡ ዮሴፍ ፡ ሂዱ ÷ እርሱ ፡ ያላችሁንም ፡ ሁሉ ፡ አድርጉ ፡ ፶፮ አላቸው ። በምድርም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ራብ ፡ ሆነ ፤ ዮሴፍም ፡ እህል ፡ ያለበትን ፡ ጎተራ ፡ ሁሉ ፡ ከፍቶ ፡ ለግብፅ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይሸጥ ፡ ነበር ፤ ራብም ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ጸንቶ ፡ ነበር ። ፶፯ አገሮችም ፡ ሁሉ ፡ እህል ፡ ይገዙ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ወደ ፡ ዮሴፍ ፡ መጡ ፤ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ራብ ፡ እጅግ ፡ ጸንቶ ፡ ነበርና ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፪ ።

፩ ያዕቆብም ፡ በግብፅ ፡ እህል ፡ እንዳለ ፡ ሰማ ÷ ያዕቆብም ፡ ልጆቹን ፡— ለምን ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ትተያያላችሁ? አላቸው ። ፪ እንዲህም ፡ አለ ፡— እነሆ ፡ ስንዴ ፡ በግብፅ ፡ እንዲገኝ ፡ ሰምቼአለሁ ፤ ወደዚያ ፡ ውረዱ ÷ እንድንድንና ፡ እንዳንሞትም ፡ ከዚያ ፡ ሸምቱልን ። ፫ የዮሴፍም ፡ አሥሩ ፡ ወንድሞቹ ፡ ስንዴን ፡ ከግብፅ ፡ ይሸምቱ ፡ ዘንድ ፡ ወረዱ ፤ ፬ የዮሴፍን ፡ ወንድም ፡ ብንያምን ፡ ግን ፡ ያዕቆብ ፡ ከወንድሞቹ ፡ ጋር ፡ አልሰደደውም ፡— ምናልባት ፡ ክፉ ፡ እንዳያገኘው ፡ ብሎአልና ። ፭ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ለእህል ፡ ሸመታ ፡ ከመጡቱ ፡ ጋር ፡ ገቡ ፤ በከነዓን ፡ አገር ፡ ራብ ፡ ነበረና ። ፮ ዮሴፍም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ገዥ ፡ ነበረ ÷ እርሱም ፡ ለምድር ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ይሸጥ ፡ ነበር ፤ የዮሴፍም ፡ ወንድሞች ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በግምባራቸው ፡ ሰገዱለት ። ፯ ዮሴፍም ፡ ወንድሞቹን ፡ አይቶ ፡ አወቃቸው ፤ ተለወጠባቸውም ÷ ክፉ ፡ ቃልንም ፡ ተናገራቸው ፡— እናንተ ፡ ከወዴት ፡ መጣችሁ ? አላቸው ። እነርሱም ፡— ከከነዓን ፡ ምድር ፡ እህል ፡ ልንሸምት ፡ የመጣን ፡ ነን ፡ አሉት ። ፰ ዮሴፍም ፡ ወንድሞቹን ፡ አወቃቸው ÷ እነርሱ ፡ ግን ፡ አላወቁትም ፤ ፱ ዮሴፍም ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ አይቶት ፡ የነበረውን ፡ ሕልም ፡ አሰበ ። እንዲህም ፡ አላቸው ፡— እናንተ ፡ ሰላዮች ፡ ናችሁ ፤ የምድሩን ፡ ዕራቁትነት ፡ ልታዩ ፡ መጥታችኋል ። ፲ እነርሱም ፡ አሉት ፡— ጌታችን ፡ ሆይ ፡ አይደለም ፤ ባሪያዎችህስ ፡ ስንዴን ፡ ሊገዙ ፡ መጥተዋል ፤ ፲፩ እኛ ፡ ሁላችን ፡ የአንድ ፡ ሰው ፡ ልጆች ፡ ነን ፤ እኛ ፡ እውነተኞች ፡ ነን ÷ ባሪያዎችህስ ፡ ሰላዮች ፡ አይደሉም ። ፲፪ እርሱም ፡ አላቸው ፡— አይደለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የአገሩን ፡ ዕራቁትነት ፡ ልታዩ ፡ መጥታችኋል ። ፲፫ እነርሱም ፡ አሉ ፡— ባሪያዎችህ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ወንድማማች ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ የአንድ ፡ ሰው ፡ ልጆች ፡ ነን ፤ ታናሹም ፡ እነሆ ፡ ዛሬ ፡ ከአባታችን ፡ ጋር ፡ ነው ÷ አንዱም ፡ ጠፍቶአል ። ፲፬ ዮሴፍም ፡ አላቸው ፡— እናንተ ፡ ሰላዮች ፡ ናችሁ ፡ ብዬ ፡ የተናገርኋችሁ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ፲፭ በዚህ ፡ ትፈተናላችሁ ፤ ታናሽ ፡ ወንድማችሁ ፡ ከልመጣ ፡ በቀር ፡ የፈርዖንን ፡ ሕይወት ፡ ከዚህ ፡ አትወጡም ። ፲፮ እውነትን ፡ የምትናገሩ ፡ ከሆነ ፡ ነገራችሁ ፡ ይፈተን ፡ ዘንድ ፡ ከእናንተ ፡ አንዱን ፡ ስደዱ ÷ ወንድማችሁንም ፡ ይዞ ፡ ይምጣ ÷ እናንተም ፡ ታስራችሁ ፡ ተቀመጡ ፤ ይህ ፡ ካልሆነ ፡ የፈርዖንን ፡ ሕይወት ፡ ሰላዮች ፡ ናችሁ ። ፲፯ ሦስት ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ በግዞት ፡ ቤት ፡ ጨመራቸው ።

፲፰ ፡ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ዮሴፍ ፡ እንዲህ ፡ አላ
ቸው ፡— ትድኑ ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡ አድርጉ ፤ እኔ ፡
፲፱ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እፈራለሁና ። እናንተ ፡ የታ
መናችሁ ፡ ከሆናችሁ ፡ ከእናንተ ፡ አንዱ ፡ ወን
ድማችሁ ፡ በግዞታችሁ ፡ ቤት ፡ ይታሰር ፤ እና
ንተ ፡ ግን ፡ ሂዱ ÷ እህሉንም ፡ ለቤታችሁ ፡ ራብ ፡
፳ ፡ ውሰዱ ፤ ታናሹንም ፡ ወንድማችሁን ፡ ወደ ፡
እኔ ፡ ይዛችሁ ፡ ኑ ፤ ነገራችሁም ፡ የታመነ ፡ ይሆ
ናልና ፡ አትሞቱም ። እንዲህም ፡ አደረጉ ።
፳፩ ፡ እነርሱም ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ እንዲህ ፡ ተባ
ባሉ ፡— በእውነት ፡ ወንድማችንን ፡ በድለናል ÷
እኛን ፡ በማማጠን ፡ ነፍሱ ፡ ስትጨነቅ ፡ አይተን ፡
አልሰማነውምና ፤ ስለዚህ ፡ ይህ ፡ መከራ ፡ መጣ
፳፪ ፡ ብን ። ሮቤልም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡—
ብላቴናውን ፡ አትበድሉ ፡ ብያችሁ ፡ አልነበረ
ምን ? እኔንም ፡ አልሰማችሁኝም ፤ ስለዚህ ፡
፳፫ ፡ እነሆ ፡ አሁን ፡ ደሙ ፡ ይፈላለገናል ። እነር
ሱም ፡ ዮሴፍ ፡ ነገራቸውን ፡ እንደሚሰማባቸው ፡
አላወቁም ÷ በመካከላቸው ፡ አስተርጓሚ ፡ ነበ
፳፬ ፡ ረና ። ከእነርሱም ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ አለቀሰ ፤
ደግሞም ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ተመልሶ ፡ ተናገራ
ቸው ÷ ስምዖንንም ፡ ከእነርሱ ፡ ለይቶ ፡ ወስዶ ፡
፳፭ ፡ በፊታቸው ፡ አሰረው ። ዮሴፍም ፡ ዓይበታቸ
ውን ፡ እህል ፡ ይሞሉት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ የእየራሳ
ቸውንም ፡ ብር ፡ በእየዓይበታቸው ፡ ይመልሱት ፡
ዘንድ ፡ ደግሞም ፡ የመንገድ ፡ ስንቅ ፡ ይሰጡአ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ። እንዲሁም ፡ ተደረገላ
ቸው ።

፳፮ ፡ እነርሱም ፡ እህሉን ፡ በአህዮቻቸው ፡ ላይ ፡
፳፯ ፡ ጫኑ ÷ ከዚያም ፡ ተነሥተው ፡ ሄዱ ። ከእነር
ሱም ፡ አንዱ ፡ ባደሩበት ፡ ስፍራ ፡ ለአህያው ፡
ገፈራን ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ዓይበቱን ፡ ሲፈታ ፡
ብሩን ፡ አየ ÷ እነሆም ፡ በዓይበቱ ፡ አፍ ፡ ላይ ፡
፳፰ ፡ ነበረች ። ለወንድሞቹም ፡— ብሬ ፡ ተመለሰ
ችልኝ ÷ እርስዋም ፡ በዓይበቴ ፡ አፍ ፡ እነኋት ፡
አላቸው ። ልባቸውም ፡ ደነገጠ ÷ እየተንቀጠ
ቀጡም ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተባባሉ ፡— እግዚ
አብሔር ፡ ያደረገብን ፡ ይህ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
፳፱ ፡ ወደ ፡ አባታቸውም ፡ ወደ ፡ ያዕቆብ ፡ ወደ ፡ ከነ
ዓን ፡ ምድር ፡ መጡ ÷ የደረሰባቸውንም ፡ ነገር ፡
፴ ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ አወሩ ፡— የአገሩ ፡
ጌታ ፡ የሆነው ፡ ሰው ፡ በክፉ ፡ ንግግር ፡ ተናገ
ረን ÷ የምድሪቱም ፡ ሰላዮች ፡ አስመሰለን ።
፴፩ ፡ እኛም ፡ እንዲህ ፡ አልነው ፡— እውነተኞች ፡
ሰዎች ፡ ነን ፡ እንጂ ፡ ሰላዮች ፡ አይደለንም ፤
፴፪ ፡ እኛ ፡ የአባታችን ፡ ልጆች ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡
ወንድማማች ፡ ነን ፤ አንዱ ፡ ጠፍቶአል ÷ ታና
ሹም ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ዛሬ ፡ ከአባታችን ፡
፴፫ ፡ ጋር ፡ አለ ። የአገሩም ፡ ጌታ ፡ ያ ፡ ሰው ፡ እን
ዲህ ፡ አለን ፡— የታመናችሁ ፡ ሰዎች ፡ ከሆና
ችሁ ፡ በዚህ ፡ አውቃለሁ ፤ አንደኛውን ፡ ወን
ድማችሁን ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ተዉት ÷ ለቤታች
፴፬ ፡ ሁም ፡ ራብ ፡ እህልን ፡ ወስዳችሁ ፡ ሂዱ ፤ ታና
ሹንም ፡ ወንድማችሁን ፡ አምጡልኝ ÷ እውነ
ተኞች ፡ እንጂ ፡ ሰላዮች ፡ አለመሆናችሁንም ፡
በዚህ ፡ አውቀዋለሁ ፤ ወንድማችሁንም ፡ እሰ
ጣችኋለሁ ÷ እናንተም ፡ በምድሩ ፡ ትነግዳላ
ችሁ ።

፴፭ ፡ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ዓይበታቸውን ፡ በፈቱ ፡
ጊዜ ፡ እነሆ ፡ ከእነርሱ ፡ እያንዳንዳቸው ፡ ብራቸ
ውን ፡ በእየዓይበታቸው ፡ ተቋጥሮ ፡ አገኙት ፤ እነ
ርሱም ፡ አባታቸውም ፡ የብራቸውን ፡ ቋጥራት ፡
፴፮ ፡ አይተው ፡ ፈሩ ። አባታቸው ፡ ያዕቆብም ፡ እን
ዲህ ፡ አላቸው ፡— ልጅ ፡ አልባ ፡ አስቀራችሁኝ ፤
ዮሴፍ ፡ የለም ÷ ስምዖንም ፡ የለም ÷ ብንያም
ንም ፡ ትወስዱብኛላችሁ ፤ ይህ ፡ ሁሉ ፡ በእኔ ፡
፴፯ ፡ ላይ ፡ ደረሰ ። ሮቤልም ፡ አባቱን ፡ አለው ፡—
ወደ ፡ አንተ ፡ መልሼ ፡ ያላመጣሁት ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ ሁለቱን ፡ ልጆቼን ፡ ግደል ፤ እርሱን ፡ በእጄ ፡
ስጠኝ ÷ እኔም ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እመልሰዋለሁ ።
፴፰ ፡ እርሱም ፡ አለ ፡— ልጄ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ አይወ
ርድም ፤ ወንድሙ ፡ ሞቶ ፡ እርሱ ፡ ብቻ ፡ ቀር
ቶአልና ፤ በምትሄዱበት ፡ መንገድ ፡ ምናልባት ፡
ክፉ ፡ ነገር ፡ ቢያገኘው ፡ ሽምግልናዬን ፡ በኀዘን ፡
ወደ ፡ መቃብር ፡ ታወርዱታላችሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፫ ።

፩ ፡ ፪ ፡ ራብም ፡ በምድር ፡ ጸና ። ከግብፅም ፡ ያመ
ጡትን ፡ እህል ፡ በልተው ፡ ከፈጸሙ ፡ በኋላ ፡
አባታቸው ፡— እንደ ፡ ገና ፡ ሂዱ ፤ ጥቂት ፡
፫ ፡ እህል ፡ ሸምቱልን ፡ አላቸው ። ይሁዳም ፡ እን
ዲህ ፡ አለው ፡— ያ ፡ ሰው ፡— ወንድማችሁ ፡
ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ከልሆነ ፡ ፊቴን ፡ አታዩም ፡
፬ ፡ ብሎ ፡ በብርቱ ፡ ቃል ፡ አስጠነቀቀን ። ወንድማ
ችንን ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ብትሰድደው ፡ እንወርዳ
፭ ፡ ለን ÷ እህልም ፡ እንሸምትልሃለን ፤ ባትሰድደው ፡
ግን ፡ አንሄድም ፤ ያ ፡ ሰው ፡— ወንድማችሁ ፡
ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ከልሆነ ፡ ፊቴን ፡ አታዩም ፡
፮ ፡ ብሎናልና ። እስራኤልም ፡ አላቸው ፡— ለምን ፡
በደላችሁኝ ? ለዚያውስ ፡— ሌላ ፡ ወንድም ፡
፯ ፡ አለን ፡ ብላችሁ ፡ ለምን ፡ ነገራችሁት ? እነር
ሱም ፡ አሉ ፡— ያ ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ እኛና ፡ ስለ ፡ ወገ
ናችን ፡ ፈጽሞ ፡ ጠየቀን ፡ እንዲህም ፡ አለን ፡—
አባታችሁ ፡ ገና ፡ በሕይወት ፡ ነው ? ወንድምስ ፡
አላችሁን ? እኛም ፡ እንደዚሁ ፡ እንደ ፡ ጥያ
ቄው ፡ መለስንለት ፤ በውኑ ፡— ወንድማችሁን ፡
፰ ፡ አምጡ ፡ እንዲለን ፡ እናውቅ ፡ ነበርንን ? ይሁ
ዳም ፡ አባቱን ፡ እስራኤልን ፡ አለው ፡— እኛና ፡
አንተ ፡ ልጆቻችንም ፡ ደግሞ ፡ እንድንድን ፡
እንዳንሞትም ፡ ብላቴናውን ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ስደ
፱ ፡ ደው ÷ እኛም ፡ ተነሥተን ፡ እንሄዳለን ። እኔ ፡
ስለ ፡ እርሱ ፡ እዋሳለሁ ፡ ከእጄ ፡ ትሻዋለህ ፤
ወደ ፡ አንተ ፡ ባላመጣው ÷ በፊትህም ፡ ባላቆ
መው ÷ በዘመናት ፡ ሁሉ ፡ አንተን ፡ የበደልሁ ፡
፲ ፡ ልሁን ። ባንዘገይስ ፡ ኖሮ ፡ አሁን ፡ ሁለተኛ ፡
፲፩ ፡ ጊዜ ፡ በተመለስን ፡ ነበር ። እስራኤልም ፡ አባ
ታቸው ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— ነገሩ ፡ እንዲህ ፡
ከሆነስ ፡ ይህንን ፡ አድርጉ ፤ ከተመሰገነው ፡

ከምድሩ ፡ ፍሬ ፡ በዓይበታችሁ ፡ ይዛችሁ ፡ ሂዱ ÷
ለዚያም ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ መንሻ ÷ ጥቂት ፡ በለሳን ÷
ጥቂት ፡ ማር ÷ ሽቱ ÷ ከርቤ ÷ ተምር ÷ ለውዝ ፡
፲፪ ውሰዱ ። ብሩን ፡ በአጠፌታ ፡ አድርጋችሁ ፡
በእጃችሁ ፡ ውሰዱ ፤ በዓይበታችሁ ፡ አፍ ፡ የተ
መለሰውንም ፡ ብር ፡ መልሳችሁ ፡ ውሰዱ ፤ ምና
፲፫ ልባት ፡ በስሕተት ፡ ይሆናል ። ወንድማችሁ
ንም ፡ ውሰዱ ÷ ተነሥታችሁም ፡ ወደዚያ ፡ ሰው ፡
፲፬ ተመለሱ ። ሁሉን ፡ የሚችል ፡ አምላክም ፡ ሌላ
ውን ፡ ወንድማችሁንና ፡ ብንያምን ፡ ከእናንተ ፡
ጋር ፡ ይሰድድ ፡ ዘንድ ፡ በዚያ ፡ ሰው ፡ ፊት ፡ ምሕ
ረትን ፡ ይስጣችሁ ፤ እኔም ፡ ልጆቼን ፡ እንዳጣሁ ፡
፲፭ አጣሁ ። ሰዎቹም ፡ በእጃቸው ፡ ያችን ፡ እጅ ፡ መን
ሻና ፡ አጠፌታውን ፡ ብር ፡ ብንያምንም ፡ ወሰዱ ፤
ተነሥተውም ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ወረዱ ÷ በዮሴ
ፍም ፡ ፊት ፡ ቆሙ ።

፲፮ ዮሴፍም ፡ ብንያምን ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ በየው ፡
ጊዜ ፡ የቤቱን ፡ አዛዥ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘ
ዘው ፡ — እነዚያን ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ አስገ
ባቸው ÷ እርድም ፡ እረድ ፡ አዘጋጅም ÷ እነዚያ ፡
ሰዎች ፡ በእኩለ ፡ ቀን ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ይበላሉና ።
፲፯ ያ ፡ ሰውም ፡ ዮሴፍ ፡ እንዳለው ፡ አደረገ ፤ ያ ፡
ሰውም ፡ ሰዎቹን ፡ ወደ ፡ ዮሴፍ ፡ ቤት ፡ አስገባ ።
፲፰ እነርሱም ፡ ወደ ፡ ዮሴፍ ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ ገቡ ፡
ፈሩ ፤ እንዲህም ፡ አሉ ፡ — በዓይበታችን ፡
ቀድሞ ፡ ስለ ፡ ተመለሰው ፡ ብር ፡ ሊተነኰልብን ፡
ሊወድቅብንም ÷ እኛንም ፡ በባርነት ፡ ሊገዛ ፡
አህዮቻችንንም ፡ ሊወስድ ፡ ወደዚህ ፡ አስገባን ።
፲፱ ወደ ፡ ዮሴፍ ፡ ቤት ፡ አዛዥም ፡ ቀረቡ ÷ በቤ
፳ ቱም ፡ ደጅ ፡ ተናገሩት ÷ እንዲህም ፡ አሉት ፡ —
ጌታዬ ፡ ሆይ ÷ ቀድሞ ፡ እህልን ፡ ልንሸምት ፡
፳፩ ወርደን ፡ ነበር ፤ ወደምናድርበትም ፡ ስፍራ ፡
በደረስን ፡ ጊዜ ፡ ዓይበታችንን ፡ ከፈትን ÷ እነ
ሆም ÷ የእያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ ብር ፡ በየዓይበቱ ፡
አፍ ፡ እንደ ፡ ሚዛኑ ፡ ብራችን ፡ ነበረ ፤ አሁንም ፡
፳፪ በእጃችን ፡ መለስነው ። እህል ፡ እንሸምትበት ፡
ዘንድ ፡ ሌላም ፡ ብር ፡ በእጃችን ፡ አመጣን ፤ ብራ
ችንንም ፡ በዓይበታችን ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ጨመ
፳፫ ረው ፡ አናውቅም ። እርሱም ፡ አላቸው ፡ —
ሰላም ፡ ለእናንተ ፡ ይሁን ÷ አትፍሩ ፤ አምላካች
ሁና ፡ የአባታችሁ ፡ አምላክ ፡ በዓይበታችሁ ፡
የተሰወረ ፡ ገንዘብ ፡ ሰጣችሁ ፤ ብራችሁስ ፡ ደር
፳፬ ሶኛል ። ስምዖንንም ፡ አወጣላቸው ። ሰውዮ
ውም ፡ እነዚያን ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ዮሴፍ ፡ ቤት ፡
አስገባቸው ፤ ውኃ ፡ አመጣላቸው ÷ እግራቸ
ውንም ፡ ታጠቡ ፤ ለአህዮቻቸው ፡ አበቅ ፡ ሰጣ
፳፭ ቸው ። ዮሴፍም ፡ በእኩለ ፡ ቀን ፡ እስኪገባ ፡
ድረስ ፡ እነርሱ ፡ እጅ ፡ መንሻቸውን ፡ አዘጋጁ ÷
ከዚያ ፡ እንጀራን ፡ እንደሚበሉ ፡ ሰምተዋልና ።

፳፮ ዮሴፍም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ በእጃቸው ፡
ያለውን ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ በቤት ፡ ውስጥ ፡ አቀረ
ቡለት ÷ ወደ ፡ ምድርም ፡ ወድቀው ፡ ሰገዱለት ።
፳፯ እርሱም ፡ ደኅንነታቸውን ፡ ጠየቃቸው ÷ እንዲ
ህም ፡ አለ ፡ — የነገራችሁኝ ፡ ሽማግሌ ፡ አባታ
ችሁ ፡ ደኅና ፡ ነውን ? ገና ፡ በሕይወት ፡ አለን ?
፳፰ እነርሱም ፡ አሉት ፡ — ባሪያህ ፡ አባታችን ፡ ደኅና ፡
ነው ፤ ገና ፡ በሕይወት ፡ አለ ። አጐንብሰውም ፡
፳፱ ሰገዱለት ። ዓይኑንም ፡ አንሥቶ ፡ የእናቱን ፡ ልጅ ፡
ብንያምን ፡ አየው ÷ እርሱም ፡ አለ ፡ — የነገራች
ሁኝ ፡ ታናሽ ፡ ወንድማችሁ ፡ ይህ ፡ ነውን ? እን
ዲህም ፡ አለው ፡ — ልጄ ፡ ሆይ ÷ እግዚአብሔር ፡
፴ ይባርክህ ። ዮሴፍም ፡ ቸኰለ ÷ አንጀቱ ፡ ወንድ
ሙን ፡ ናፍቆታልና ፤ ሊያለቅስም ፡ወደደ ፤ ወደ ፡
፴፩ እልፍኙም ፡ ገብቶ ፡ ከዚያ ፡ አለቀሰ ። ፊቱንም ፡
ታጥቦ ፡ ወጣ ÷ ልቡንም ፡ አስታግሦ ፡ — እንጀራ ፡
፴፪ አቅርቡ ፡ አለ ። ለእርሱም ፡ ለብቻው ፡ አቀ
ረቡ ÷ ለእነርሱም ፡ ለብቻቸው ÷ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
ለሚበሉት ፡ ለግብፅ ፡ ሰዎችም ፡ ለብቻቸው ፤
የግብፅ ፡ ሰዎች ፡ ከዕብራውያን ፡ ጋር ፡ መብላት ፡
አይሆንላቸውምና ÷ ይህ ፡ ለግብፅ ፡ ሰዎች ፡
፴፫ እንደ ፡ መርከስ ፡ ነውና ። በፊቱም ፡ በኵሩ ፡
እንደ ፡ ታላቅነቱ ፡ ታናሹም ፡ እንደ ፡ ታናሽነቱ ፡
ተቀመጡ ፤ ሰዎቹም ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተደ
፴፬ ነቁ ። በፊቱም ፡ ከለው ፡ መብል ፡ ፈንታቸውን ፡
አቀረበላቸው ፤ የብንያምም ፡ ፈንታ ፡ ከሁሉ ፡
አምስት ፡ እጅ ፡ የሚበልጥ ፡ ነበረ ። እነርሱም ፡
ጠጡ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ደስ ፡ አላቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፬ ።

፩ ዮሴፍም ፡ የቤቱን ፡ አዛዥ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
አዘዘ ፡ — ዓይበታቸው ፡ የሚያነሣውን ፡ ያህል ፡
እህል ፡ ሙላቸው ÷ የሁሉንም ፡ ብር ፡ በየዓ
፪ ይበታቸው ፡ አፍ ፡ ጨምረው ፤ በታናሹም ፡
ዓይበት ፡ አፍ ፡ የብሩን ፡ ጽዋዬንና ፡ የእህሉን ፡
ዋጋ ፡ ጨምረው ። እርሱም ፡ ዮሴፍ ፡ እንዳ
፫ ለው ፡ አደረገ ። ነግህ ፡ በሆነ ፡ ጊዜም ፡ ሰዎቹ ፡
አህዮቻቸውን ፡ ይዘው ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ተሰና
፬ በቱ ። ከከተማይቱም ፡ ወጥተው ፡ ገና ፡ ሳይርቁ ፡
ዮሴፍ ፡ ለቤቱ ፡ አዛዥ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡ — ተነሥ
ተህ ፡ ሰዎቹን ፡ ተከተላቸው ፤ በደረስህባቸውም ፡
ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ በላቸው ፡ — በመልካሙ ፡ ፋንታ ፡
፭ ስለ ፡ ምን ፡ ክፉን ፡ መለሳችሁ ? ጌታዬ ፡ የሚ
ጠጣበት ፡ ምሥጢርንም ፡ የሚያውቅበት ፡
ጽዋ ፡ አይደለምን ? ባደረጋችሁት ፡ ነገር ፡ በደላ
፮ ችሁ ። እርሱም ፡ደረሰባቸው ፡ ይህንም ፡ ቃል ፡
፯ ነገራቸው ። እነርሱም ፡ አሉት ፡ — ጌታዬ ፡ እን
ደዚህ ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ ለምን ፡ ይናገራል ? ባሪ
ያዎችህ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ የሚያደርጉ ፡ አይደ
፰ ሉም ። እነሆ ÷ በዓይበታችን ፡ አፍ ፡ ያገኘነውን ፡
ብር ፡ ይዘን ፡ ከከነዓን ፡ አገር ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ተመ
ልሰናል ፤ ከጌታህ ፡ ቤት ፡ ወርቅ ፡ ወይስ ፡ ብር ፡
፱ እንዴት ፡ እንሰርቃለን ? ከባሪያዎችህ ፡ ጽዋው ፡
የተገኘበት ፡ እርሱ ፡ ይሙት ፤ እኛም ፡ ደግሞ ፡
፲ ለጌታችን ፡ ባሪያዎች ፡ እንሁን ። እርሱም ፡
አለ ፡ — አሁንም ፡ እንዲሁ ፡ እንደ ፡ ነገራችሁ ፡
ይሁን ፤ ጽዋው ፡ የተገኘበት ፡ እርሱ ፡ ለእኔ ፡
ባሪያ ፡ ይሁነኝ ÷ እናንተም ፡ ንጹሐን ፡ ትሆናላ
፲፩ ችሁ ። እየራሳቸውም ፡ ፈጥነው ፡ ዓይበታቸ

ውን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ አወረዱ ÷ እየራሳቸውም ፡
፲፪ ዓይበታቸውን ፡ ፈቱ ። እርሱም ፡ ከታላቁ ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታናሹ ፡ ድረስ ፡ በረበራቸው ÷
ጽዋውንም ፡ በብንያም ፡ ዓይበት ፡ ውስጥ ፡ አገ
፲፫ ኘው ። ልብሳቸውንም ፡ ቀደዱ ÷ ዓይበታቸው
ንም ፡ በየአህዮቻቸው ፡ ጭነው ፡ ወደ ፡ ከተማ
ይቱ ፡ ተመለሱ ።
፲፬ ይሁዳም ፡ ከወንድሞቹ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ዮሴፍ ፡
ገባ ÷ እርሱም ፡ ገና ፡ ከዚያው ፡ ነበረ ፤ በፊ
፲፭ ቱም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ወደቁ ። ዮሴፍም ፦
ይህ ፡ ያደረጋችሁት ፡ ነገር ፡ ምንድር ፡ ነው ?
እንደ ፡ እኔ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ምሥጢርን ፡ እንዲያ
፲፮ ውቅ ፡ አታውቁምን ? አላቸው ። ይሁዳም ፡
አለ ፦ ለጌታዬ ፡ ምን ፡ እንመልሳለን ? ምንስ ፡
እንናገራለን ? ወይስ ፡ በምን ፡ እንነጻለን ? እግ
ዚአብሔር ፡ የባሪያዎችህን ፡ ኃጢአት ፡ገለጠ ፤
እነሆ ÷ እኛም ፡ ጽዋው ፡ ከእርሱ ፡ ዘንድ ፡ የተ
፲፯ ገኘበቱም ፡ ደግሞ ፡ ለጌታዬ ፡ ባሪያዎቹ ፡ ነን ። እር
ሱም ፡ አላቸው ፦ ይህን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ አይ
ሆንልኝም ፤ ጽዋው ፡ የተገኘበቱ ፡ ሰው ፡ እርሱ ፡
ባሪያ ፡ ይሁነኝ ፤ እናንተም ፡ ወደ ፡ አባታችሁ ፡
በደኅና ፡ ውጡ ።
፲፰ ይሁዳም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀረበ ፡ እንዲህም ፡
አለ ፦ ጌታዬ ፡ ሆይ ÷ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ በጌታዬ ፡
ጆሮ ፡ አንዲት ፡ ቃልን ፡ እንድናገር ፡ እለምና
ለሁ ፤ እኔንም ፡ ባሪያህን ፡ አትቈጣኝ ፤ አንተ ፡
፲፱ እንደ ፡ ፈርዖን ፡ ነህና ። ጌታዬ ፡ ባሪያዎቹን ፦
አባት ፡ አላችሁን ፡ ወይስ ፡ ወንድም ? ብሎ ፡
፳ ጠየቀ ። እኛም ፡ ለጌታዬ ፡ እንዲህ ፡ አልነ ፦
ሽማግሌ ፡ አባት ፡ አለን ÷ በሽምግልናው ፡ የወ
ለደውም ፡ ታናሽ ፡ ብላቴና ፡ አለ ፤ ወንድሙም ፡
ሞተ ÷ ከእናቱም ፡ እርሱ ፡ ብቻውን ፡ ቀረ ÷ አባ
፳፩ ቱም ፡ ይወድደዋል ። አንተም ፡ ለባሪያዎችህ ፦
ወደ ፡ እኔ ፡ አምጡት ÷ እኔም ፡ አየዋለሁ ፡ አልህ ።
፳፪ ጌታዬንም ፦ ብላቴናው ፡ አባቱን ፡ መተው ፡
አይሆንለትም ፤ የተወው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አባቱ ፡
፳፫ ይሞታልና ፡ አልነው ። ባሪያዎችህንም ፦
ታናሽ ፡ ወንድማችሁ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ካል
መጣ ፡ዳግመኛ ፡ ፊቴን ፡ አታዩም ፡ አልኸን ።
፳፬ ወደ ፡ ባሪያህ ፡ ወደ ፡ አባታችን ፡ በተመለስን ፡
፳፭ ጊዜም ፡ የጌታዬን ፡ ቃል ፡ ነገርነው ። አባታች
ንም ፦ ተመልሳችሁ ፡ ጥቂት ፡ እህል ፡ ሸምቱ
፳፮ ልን ፡ አለ ። እኛም ፡ አልነው ፦ እንሄድ ፡ ዘንድ ፡
አይሆንልንም ፤ ታናሹ ፡ ወንድማችን ፡ ከእኛ ፡
ጋር ፡ ይወርድ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እኛም ፡ እንወርዳ
ለን ፤ ታናሹ ፡ ወንድማችን ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ከሌለ ፡
የዚያን ፡ ሰው ፡ ፊት ፡ ማየት ፡ አይቻለንምና ።
፳፯ ባሪያህ ፡ አባቴም ፡ እንዲህ ፡ አለን ፦ ሚስቴ ፡
ሁለት ፡ ወንዶች ፡ ልጆችን ፡ እንደ ፡ ወለደች
፳፰ ልኝ ፡ እናንተ ፡ታውቃላችሁ ፤ አንዱም ፡ ከእኔ ፡
ወጣ ፦ አውሬ ፡ በላው ፡ አላችሁኝ ÷ እስከ ፡
፳፱ ዛሬም ፡ አላየሁትም ፤ ይህንም ፡ ከእኔ ፡ ለይታ
ችሁ ፡ ደግሞ ፡ ብትወስዱት ፡ ክፉም ፡ ቢያገ
ኘው ÷ ሽበቴን ፡ በኀዘን ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ታወ
ርዱታላችሁ ። አሁንም ፡ እኔ ፡ ወደ ፡ አባቴ ፡ ፴
ወደ ፡ ባሪያህ ፡ ብሄድ ÷ ብላቴናውም ፡ ከእኛ ፡
ጋር ፡ ከሌለ ÷ ነፍሱ ፡ በብላቴናው ፡ነፍስ ፡ ታስ
ራለችና ፡ ብላቴናው ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ እንደሌለ ፡ ፴፩
በየ ፡ ጊዜ ፡ ይሞታል ፤ ባሪያዎችህም ፡ የባሪያ
ህን ፡ የአባታችንን ፡ ሽበት ፡ በኀዘን ፡ ወደ ፡ መቃ
ብር ፡ ያወርዳሉ ። እኔ ፡ ባሪያህ ፡ በአባቴ ፡ ዘንድ ፡ ፴፪
ስለ ፡ ብላቴናው ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ ተውሼአለ
ሁና ፦ እርሱንስ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ባላመጣው ፡
በአባቴ ፡ ዘንድ ፡ በዘመናት ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአተኛ ፡
እሆናለሁ ። ስለዚህም ፡ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ በጌ ፴፫
ታዬ ፡ ዘንድ ፡ ባሪያ ፡ ሆኜ ፡ በብላቴናው ፡ ፋንታ ፡
ልቀመጥ ፤ ብላቴናውም ፡ ከወንድሞቹ ፡ ጋር ፡
ይውጣ ። አለዚያም ፡ ብላቴናው ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ፴፬
ከሌለ ፡ ወደ ፡ አባቴ ፡ እንዴት ፡ እወጣለሁ ? አባ
ቴን ፡ የሚያገኘውን ፡ መከራ ፡ እንዳላይ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፭ ።

፩ ዮሴፍም ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ቆመው ፡ በሉት ፡
ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ሊታገሥ ፡ አልተቻለውም ፦
ሰዎቹንም ፡ ሁሉ ፡ ከፊቴ ፡ አስወጡልኝ ፡ ብሎ ፡
ጮኸ ፡ ተናገረ ፤ ዮሴፍ ፡ ለወንድሞቹ ፡ ራሱን ፡
በገለጠ ፡ ጊዜ ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ የቆመ ፡ ማንም ፡
፪ አልነበረም ። ቃሉንም ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡ አለ
ቀሰ ፤ የግብፅ ፡ ሰዎችም ፡ ሰሙ ÷ በፈርዖን ፡
፫ ቤትም ፡ ተሰማ ። ዮሴፍም ፡ ለወንድሞቹ ፦
እኔ ፡ ዮሴፍ ፡ ነኝ ፤ አባቴ ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ በሕ
ይወቱ ፡ ነውን ? አለ ። ወንድሞቹም ፡ ይመ
ልሱለት ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉም ÷ በፊቱ ፡ ደንግ
፬ ጠው ፡ ነበርና ። ዮሴፍም ፡ ወንድሞቹን ፦ ወደ ፡
እኔ ፡ ቅረቡ ፡ አለ ። ወደ ፡ እርሱም ፡ ቀረቡ ።
እንዲህም ፡ አላቸው ፦ ወደ ፡ ግብፅ ፡ የሸጣች
፭ ሁኝ ፡ እኔ ፡ ወንድማችሁ ፡ ዮሴፍ ፡ ነኝ ። አሁ
ንም ፡ ወደዚህ ፡ ስለ ፡ ሸጣችሁኝ ፡ አትዘኑ ÷ አት
ቈርቈሩም ፤ እግዚአብሔር ፡ ሕይወትን ፡ ለማ
፮ ዳን ፡ ከእናንተ ፡ በፊት ፡ ሰደደኝልና ። ይህ ፡
ሁለቱ ፡ ዓመት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ራብ ፡ የሆነ
በት ፡ ነውና ፤ የማይታረስበትና ፡ የማይታጨ
፯ ድበት ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ገና ፡ ቀረ ። እግዚ
አብሔርም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ቅሬታን ፡ አስቀር
ላችሁ ፡ ዘንድ ፡ በታላቅ ፡ መድኃኒትም ፡ አድና
፰ ችሁ ፡ ዘንድ ፡ ከእናንተ ፡ በፊት ፡ ላከኝ ። አሁ
ንም ፡ እናንተ ፡ ወደዚህ ፡ የላካችሁኝ ፡ አይደላ
ችሁም ÷ እግዚአብሔር ፡ ላከኝ ፡ እንጂ ፤ ለፈ
ርዖንም ፡ እንደ ፡ አባት ፡ አደረገኝ ÷ በቤቱም ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ ጌታ ÷ በግብፅ ፡ ምድርም ፡ ሁሉ ፡
፱ ላይ ፡ አለቃ ፡ አደረገኝ ። አሁንም ፡ ፈጥናችሁ ፡
ወደ ፡ አባቴ ፡ ውጡ ÷ እንዲህም ፡ በሉት ፦
ልጅህ ፡ ዮሴፍ ፡ የሚለው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፦
እግዚአብሔር ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡
ጌታ ፡ አደረገኝ ፤ ወደ ፡ እኔ ፡ ና ÷ አትዘግይ ፤
፲ በጌሤምም ፡ ምድር ፡ ትቀመጣለህ ÷ ወደ ፡ እኔም ፡
ትቀርባለህ ÷ አንተና ፡ ልጆችህ ፡ የልጆችህም ፡
ልጆች ÷ በጎችህና ፡ ላሞችህ ፡ ከብትህም ፡ ሁሉ ።

፲፩ በዚያም ፡ አንተና ፡ የቤትህ ፡ ሰዎች ፡ የአንተ ፡ የሆነው ፡ ሁሉ ፡ እንዳትቸገሩ ፡ እመግብሃለሁ ፡ የራቡ ፡ ዘመን ፡ ገና ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ቀርቶአ ልና ። ፲፪ እነሆም ፡ ለእናንተ ፡ የተናገረቻችሁ ፡ የእኔ ፡ አፍ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ የእናንተ ፡ ዓይኖች ፡ አይተዋል ፤ የወንድሜ ፡ የብንያምም ፡ ዓይኖች ፡ አይተዋል ። ፲፫ ለአባቴም ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ያለ ኝን ፡ ክብሬን ፡ ሁሉ ፡ ያያችሁትንም ፡ ሁሉ ፡ ንገሩት ፤ አባቴንም ፡ ወደዚህ ፡ ፈጥናችሁ ፡ አም ጡት ። ፲፬ የወንድሙን ፡ የብንያምንም ፡ አንገት ፡ አቅፎ ፡ አለቀሰ ፤ ብንያምም ፡ በአንገቱ ፡ ላይ ፡ አለቀሰ ። ፲፭ ወንድሞቹን ፡ ሁሉ ፡ ሳማቸው ፤ በእነርሱም ፡ ላይ ፡ አለቀሰ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ወንድሞቹ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተጫወቱ ።

፲፮ በፈርዖንም ፡ ቤት ፡— የዮሴፍ ፡ ወንድሞች ፡ መጡ ፡ ተብሎ ፡ ወሬ ፡ ተሰማ ፤ በዚያውም ፡ ፈርዖንና ፡ ሎሌሎቹ ፡ ደስ ፡ ተሰኙበት ። ፲፯ ፈርዖ ንም ፡ ዮሴፍን ፡ አለው ፡— ለወንድሞችህ ፡ እን ዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— ይህን ፡ አድርጉ ፤ ከብቶቻችሁን ፡ ጭናችሁ ፡ ወደ ፡ ከነዓን ፡ ምድር ፡ ፲፰ ሂዱ ፤ አባታችሁንና ፡ ቤተ ፡ ሰቦቻችሁን ፡ ይዛችሁም ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ኑ ፤ እኔም ፡ የግብፅን ፡ ምድር ፡ በረከት ፡ ሁሉ ፡ እሰጣችኋለሁ ፤ የምድሪቱ ንም ፡ ስብ ፡ ትበላላችሁ ። ፲፱ አንተም ፡ ወንድሞ ችህን ፡— እንዲህ ፡ አድርጉ ፡ በላቸው ፤ ከግ ብፅ ፡ ምድር ፡ ለሕፃናቶቻችሁ ፡ ለሴቶቻችሁም ፡ ሰረገሎችን ፡ ውሰዱ ፤ አባታችሁንም ፡ ይዛችሁ ፡ ፳ ኑ ፤ ለዕቃችሁም ፡ ሁሉ ፡ አታስቡ ፤ የግብፅ ፡ በረከት ፡ ሁሉ ፡ ለእናንተ ፡ ነውና ።

፳፩ የእስራኤል ፡ ልጆችም ፡ እንደዚሁ ፡ አደረጉ ፤ ዮሴፍም ፡ በፈርዖን ፡ ትእዛዝ ፡ ሰረገሎችንና ፡ ፳፪ ለመንገድ ፡ ስንቅ ፡ ሰጣቸው ፤ ለሁሉም ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ መለወጫ ፡ ልብስ ፡ ሰጣቸው ፤ ለብን ያም ፡ ግን ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ብርና ፡ አምስት ፡ መለ ፳፫ ወጫ ፡ ልብስ ፡ ሰጠው ። ለአባቱም ፡ እንደ ዚሁ ፡ ሰደደ ፤ የግብፅን ፡ በረከት ፡ የተሸከሙ ፡ አሥር ፡ አህዮችን ፤ ደግሞም ፡ በመንገድ ፡ ለአ ባቱ ፡ ስንቅ ፡ ስንዴና ፡ እንጀራ ፡ የተሸከሙ ፡ ፳፬ አሥር ፡ ሴቶች ፡ አህዮችን ። ዮሴፍም ፡ ወን ድሞቹን ፡ አሰናበታቸው ፤ እንዲህም ፡ አላ ቸው ፡— በመንገድ ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ አት ፳፭ ጣሉ ። እነርሱም ፡ ሄዱ ፤ ከግብፅ ፡ አገርም ፡ ወጡ ፤ ወደ ፡ ከነዓንም ፡ ምድር ፡ ከአባታቸው ፡ ፳፮ ከያዕቆብ ፡ ዘንድ ፡ ደረሱ ። እንዲህም ፡ ብለው ፡ ነገሩት ፡— ዮሴፍ ፡ ገና ፡ በሕይወቱ ፡ ነው ፤ እር ሱም ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ገዥ ፡ ሆኖ አል ። ያዕቆብም ፡ ልቡ ፡ ደነገጠ ፤ አላመናቸ ፳፯ ውም ፡ ነበርና ። እነርሱም ፡ ዮሴፍ ፡ የነገራቸ ውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ነገሩት ፤ እርሱን ፡ ያነሡት ፡ ዘንድ ፡ ዮሴፍ ፡ የሰደዳቸውን ፡ ሰረገሎች ፡ በየ ፡ ጊዜም ፡ የአባታቸው ፡ የያዕቆብ ፡ የነፍሱ ፡ ሕይ ፳፰ ወት ፡ ታደሰች ። እስራኤልም ፡— ልጄ ፡ ዮሴፍ ፡ ገና ፡ በሕይወት ፡ ከሆነ ፡ ይበቃኛል ፤ ሳልሞት ፡ እንዳየው ፡ እሄዳለሁ ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፮ ።

፩ እስራኤልም ፡ ለእርሱ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ይዞ ፡ ተነሣ ፤ ወደ ፡ ቤርሳቤህ ፡ መጣ ፤ መሥዋዕት ንም ፡ ለአባቱ ፡ ለይስሐቅ ፡ አምላክ ፡ ሠዋ ። ፪ እግ ዚአብሔርም ፡ በሌሊት ፡ ራእይ ፡— ያዕቆብ ፡ ያዕ ቆብ ፡ ብሎ ፡ ለእስራኤል ፡ ተናገረው ። እር ሱም ፡— እነሆኝ ፡ አለ ። ፫ አለውም ፡— የአባቶ ችህ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ ወደ ፡ ግብፅ ፡ መውረድ ፡ አትፍራ ፤ በዚያ ፡ ታላቅ ፡ ሕዝብ ፡ አደርግሃለሁና ። ፬ እኔ ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ አብሬህ ፡ እወርዳለሁ ፤ ከዚያም ፡ ደግሞ ፡ እኔ ፡ አወጣሃለሁ ፤ ዮሴፍም ፡ እጁን ፡ በዓይንህ ፡ ላይ ፡ ያኖራል ። ፭ ያዕቆብም ፡ ከቤርሳቤህ ፡ ተነሣ ፤ የእ ስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ያዕቆብን ፡ ይወስዱ ፡ ዘንድ ፡ ፈርዖን ፡ በሰደዳቸው ፡ ሰረገሎች ፡ አባታቸውን ፡ ያዕቆብንና ፡ ሕፃናቶቻቸውን ፡ ሴቶቻቸውንም ፡ ወሰዱ ። ፮ እንስሶቻቸውንም ፡ በከነዓን ፡ አገርም ፡ ያገኙትን ፡ ከብታቸውን ፡ ሁሉ ፡ ይዘው ፡ ያዕቆ ብና ፡ ዘሩ ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ መጡ ፤ ፯ ወንዶች ፡ ልጆቹንና ፡ የልጆቹን ፡ ወን ዶች ፡ ልጆች ፤ ሴቶች ፡ ልጆቹንና ፡ የወንዶች ፡ ልጆቹን ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፤ ዘሩንም ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ አስገባቸው ።

፰ ወደ ፡ ግብፅም ፡ የገቡት ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ያዕቆብና ፡ ልጆቹ ፤ የያዕቆብ ፡ ፱ በኵር ፡ ሮቤል ። የሮቤልም ፡ ልጆች ፤ ሄኖኅ ፤ ፲ ፈሉሶ ፤ አስሮን ፤ ከርሚ ። የስምዖን ፡ ልጆች ፤ ይሙኤል ፤ ያሚን ፤ አሃድ ፤ ያኪን ፤ ጾሐር ፤ የከነዓናዊት ፡ ልጅ ፡ ሳኡል ። ፲፩ የሌዊም ፡ ልጆች ፤ ፲፪ ጌድሶን ፤ ቀዓት ፤ ሜራሪ ። የይሁዳም ፡ ልጆች ፤ ዔር ፤ አውናን ፤ ሴሎም ፤ ፋሬስ ፤ ዛራ ፤ ዔርና ፡ አውናን ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ሞቱ ፤ የፋሬስም ፡ ፲፫ ልጆች ፡ ኤስሮም ፤ ሐሙል ። የይሳኮርም ፡ ልጆች ፤ ፲፬ ቶላ ፤ ፉዋ ፤ ዮብ ፤ ሺምሮን ። የዛብሎንም ፡ ፲፭ ልጆች ፤ ሴሬድ ፤ ኤሎን ፤ ያሕልኤል ። ልያ ፡ በመስጴጦምያ ፡ በሶርያ ፡ ለያዕቆብ ፡ የወለደቻ ቸው ፡ ልጆችና ፡ ሴቲቱ ፡ ልጅዋ ፡ ዲና ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ወንዶችም ፡ ሴቶችም ፡ ልጆችዋ ፡ ሁሉ ፡ ሠላሳ ፡ ሦስት ፡ ነፍስ ፡ ናቸው ። ፲፮ የጋድም ፡ ልጆች ፡ ጽፎን ፤ ሐጊ ፤ ሹኒ ፤ ኤስቦን ፤ ዔሪ ፤ አሮዲ ፤ አር ኤሊ ። ፲፯ የአሴርም ፡ ልጆች ፤ ዩምና ፤ የሱዋ ፤ የሱዊ ፤ በሪዓ ፤ እኅታቸው ፡ ሤራሕ ፤ የበሪዓ ፡ ልጆ ችም ፤ ሔቤር ፤ መልኪኤል ። ፲፰ ላባ ፡ ለልጁ ፡ ለልያ ፡ የሰጣት ፡ የዘለፋ ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ እነዚህን ፡ አሥራ ፡ ስድስቱን ፡ ነፍስ ፡ ለያዕ ቆብ ፡ ወለደች ። ፲፱ የያዕቆብ ፡ ሚስት ፡ የራሔል ፡ ልጆች ፡ ዮሴፍና ፡ ብንያም ፡ ናቸው ። ፳ ለዮሴ ፍም ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ምናሴና ፡ ኤፍሬም ፡ ተወለዱለት ፤ የሄልዮቱ ፡ ከተማ ፡ ካህን ፡ የጶጥ ፌራ ፡ ልጅ ፡ አስናት ፡ የወለደቻቸው ፡ ናቸው ። ፳፩ የብንያምም ፡ ልጆች ፤ ቤላ ፤ ቤኬር ፤ አስቤል ፤ የቤላ ፡ ልጆችም ፤ ጌራ ፤ ናዕማን ፤ አኪ ፤ ሮስ ፤ ማንፌን ፤ ሑፌም ፤ ጌራም ፡ አርድን ፡ ወለደ ።

፳፪ ለያዕቆብ ፡ የተወለዱለት ፡ የራሔልም ፡ ልጆች ፡
እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ሁሉም ፡ አሥራ ፡ አራት ፡
፳፫ ነፍስ ፡ ናቸው ። የዳንም ፡ ልጆች ፤ ሑሺም ።
፳፬ የንፍታሌምም ፡ ልጆች ፤ ያሕጽኤል ፥ ጉኒ ፥
፳፭ ዬጽር ፥ ሺሌም ። ላባ ፡ ለልጁ ፡ ለራሔል ፡ የሰ
ጣት ፡ የበላ ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ እነዚህ
ንም ፡ ለያዕቆብ ፡ ወለደችለት ፤ ሁሉም ፡ ሰባት ፡
፳፮ ነፍስ ፡ ናቸው ። ከያዕቆብ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡
የገቡት ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ከጕልበቱ ፡ የወጡት ፥
ከልጆቹ ፡ ሚስቶች ፡ ሌላ ፥ ሁላቸው ፡ ስድሳ ፡
፳፯ ስድስት ፡ ናቸው ። በግብፅ ፡ ምድር ፡ የተወለ
ዱለት ፡ የዮሴፍም ፡ ልጆች ፡ ሁለት ፡ ናቸው ፤
ወደ ፡ ግብፅ ፡ የገቡት ፡ የያዕቆብ ፡ ቤት ፡ ሰዎች ፡
ሁሉ ፡ ሰባ ፡ ናቸው ።

፳፰ ይሁዳንም ፡ በጌሤም ፡ እንዲቀበለው ፡ በፊቱ ፡
ወደ ፡ ዮሴፍ ፡ ላከ ፤ ወደ ፡ ጌሤም ፡ ምድርም ፡
፳፱ ደረሱ ። ዮሴፍም ፡ ሰረገላውን ፡ አዘጋጀ ፥
አባቱንም ፡ እስራኤልን ፡ ሊገናኘው ፡ ወደ ፡
ጌሤም ፡ ወጣ ፤ በየውም ፡ ጊዜ ፡ በአንገቱ ፡ ላይ ፡
ወደቀ ፥ አቅፎትም ፡ ረጅም ፡ ጊዜ ፡ አለቀሰ ።
፴ እስራኤልም ፡ ዮሴፍን ፦ አንተ ፡ ገና ፡ በሕይ
ወት ፡ ሳለህ ፡ ፊትህን ፡ አይቼአለሁና ፡ አሁን ፡
፴፩ ልሙት ፡ አለው ። ዮሴፍም ፡ ወንድሞቹንና ፡
የአባቱን ፡ ቤት ፡ ሰዎች ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦
እኔ ፡ መጥቼ ፡ ለፈርዖን ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ እነግረ
ዋለሁ ፦ በከነዓን ፡ ምድር ፡ የነበሩት ፡ ወንድ
ሞቼና ፡ የአባቴ ፡ ቤት ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጥ
፴፪ ተዋል ፤ እነርሱም ፡ በግ ፡ የሚጠብቁ ፡ ሰዎች ፡
ናቸው ፥ እንስሳ ፡ ያረቡ ፡ ነበርና ፤ በጎቻቸው
ንና ፡ ላሞቻቸውን ፡ ያላቸውንም ፡ ሁሉ ፡ አመጡ ።
፴፫ ፈርዖንም ፡ ቢጠራችሁ ፦ ተግባራችሁስ ፡ ምን
፴፬ ድር ፡ ነው ? ቢላችሁ ፥ በግ ፡ ጠባቂ ፡ ሁሉ ፡ ለግ
ብፅ ፡ ሰዎች ፡ ርኵስ ፡ ነውና ፡ በጌሤም ፡ እንድ
ትቀመጡ ፡ እንዲህ ፡ በሉት ፦ እኛ ፡ ባሪያዎ
ችህ ፡ ከብላቴናነታችን ፡ ጀምረን ፡ እስከ ፡ አሁን ፡
ድረስ ፥ እኛም ፡ አባቶቻችንም ፥ እንስሳ ፡ አር
ቢዎች ፡ ነን ።

ቍ. ፳፰ ፡ ጌሤም ፡ የሚለውን ፡ የግእዝ ፡ መጽሐፍ ፡ ራምሴ ፡ ይለዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፯ ።

፩ ዮሴፍም ፡ ገባ ፡ ለፈርዖንም ፡ ነገረው ፡ እን
ዲህ ፡ ብሎ ፦ አባቴና ፡ ወንድሞቼ ፡ በጎቻቸ
ውም ፡ ላሞቻቸውም ፡ ያላቸውም ፡ ሁሉ ፡ ከከ
ነዓን ፡ ምድር ፡ ወጡ ፤ እነርሱም ፡ እነሆ ፡ በጌ
፪ ሤም ፡ ምድር ፡ ናቸው ። ከወንድሞቹም ፡ አም
ስት ፡ ሰዎችን ፡ ወስዶ ፡ በፈርዖን ፡ ፊት ፡ አቆማ
፫ ቸው ። ፈርዖንም ፡ ወንድሞቹን ፦ ሥራችሁ ፡
ምንድር ፡ ነው ? አላቸው ። እነርሱም ፡ ፈር
ዖንን ፦ እኛ ፡ ባሪያዎችህ ፥ እኛም ፡ አባቶቻች
፬ ንም ፥ በግ ፡ አርቢዎች ፡ ነን ፡ አሉት ። ፈርዖ
ንንም ፡ እንዲህ ፡ አሉት ፦ በምድር ፡ ልንቀ
መጥ ፡ በእንግድነት ፡ መጣን ፥ የባሪያዎችህ ፡
በጎች ፡ የሚሰማሩበት ፡ ስፍራ ፡ የለምና ፤ ራብ ፡
በከነዓን ፡ ምድር ፡ እጅግ ፡ ጸንቶአልና ፤ አሁ
ንም ፡ ባሪያዎችህ ፡ በጌሤም ፡ ምድር ፡ እንድን
፭ ቀመጥ ፡ እንለምንሃለን ። ፈርዖንም ፡ ዮሴፍን ፡
ተናገረው ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፦ አባትህና ፡ ወን
፮ ድሞችህ ፡ መጥተውልሃል ፤ የግብፅ ፡ ምድር ፡
በፊትህ ፡ ናት ፤ በመልካሙ ፡ ምድር ፡ አባትህ
ንና ፡ ወንድሞችህን ፡ አኑራቸው ፤ በጌሤም ፡
ምድር ፡ ይኑሩ ፤ ከእነርሱም ፡ ውስጥ ፡ እው
ቀት ፡ ያላቸውን ፡ ሰዎች ፡ ታውቅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
በእንስሶቼ ፡ ላይ ፡ አለቆች ፡ አድርጋቸው ።
፯ ዮሴፍም ፡ ያዕቆብን ፡ አባቱን ፡ አስገብቶ ፡ በፈ
ርዖን ፡ ፊት ፡ አቆመው ፤ ያዕቆብም ፡ ፈርዖንን ፡
፰ ባረከው ። ፈርዖንም ፡ ያዕቆብን ፦ የዕድሜህ ፡
፱ ዘመን ፡ ስንት ፡ ዓመት ፡ ነው ? አለው ። ያዕቆ
ብም ፡ ለፈርዖን ፡ አለው ፦ የእንግድነቴ ፡
ዘመን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ነው ፤ የሕይ
ወቴ ፡ ዘመኖች ፡ ጥቂትም ፡ ክፉም ፡ ሆኑብኝ ፥
አባቶቼ ፡ በእንግድነት ፡ የተቀመጡበትንም ፡
፲ ዘመን ፡ አያህሉም ። ያዕቆብም ፡ ፈርዖንን ፡
፲፩ ባረከው ፡ ከፈርዖንም ፡ ፊት ፡ ወጣ ። ዮሴፍም ፡
አባቱንና ፡ ወንድሞቹን ፡ አኖረ ፥ ፈርዖን ፡ እን
ዳዘዘም ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ በተሻለችው ፡ በራ
፲፪ ምሴ ፡ ምድር ፡ ጕልትን ፡ ሰጣቸው ። ዮሴፍም ፡
ለአባቱና ፡ ለወንድሞቹ ፡ ለአባቱም ፡ ቤት ፡
ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ልጆቻቸው ፡ መጠን ፡
እህል ፡ ሰጣቸው ።

፲፫ በምድርም ፡ ሁሉ ፡ እህል ፡ አልነበረም ፥
ራብ ፡ እጅግ ፡ ጸንቶአልና ፤ ከራብም ፡ የተነሣ ፡
የግብፅ ፡ ምድርና ፡ የከነዓን ፡ ምድር ፡ ተጐዳ ።
፲፬ ዮሴፍም ፡ ከግብፅ ፡ ምድርና ፡ ከከነዓን ፡ ምድር ፡
በእህል ፡ ሸመት ፡ የተገኘውን ፡ ብሩን ፡ ሁሉ ፡
አከማቸ ፤ ዮሴፍም ፡ ብሩን ፡ ወደ ፡ ፈርዖን ፡ ቤት ፡
፲፭ አስገባው ። ብሩም ፡ በግብፅ ፡ ምድርና ፡ በከነ
ዓን ፡ ምድር ፡ አለቀ ፤ የግብፅ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ ዮሴፍ ፡ መጡ ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፦ እን
ጀራ ፡ ስጠን ፤ ስለ ፡ ምን ፡ በፊትህ ፡ እንሞታ
፲፮ ለን ? ብሩ ፡ አልቆብናልና ። ዮሴፍም ፦ ከብ
ቶቻችሁን ፡ አምጡልኝ ፤ ብር ፡ ካለቀባችሁ ፡
በከብቶቻችሁ ፡ ፋንታ ፡ እህል ፡ እሰጣችኋ
፲፯ ለሁ ፡ አለ ። ከብቶቻቸውንም ፡ ወደ ፡ ዮሴፍ ፡
አመጡ ፥ ዮሴፍም ፡ በፈረሶቻቸው ፡ በበጎቻ
ቸውም ፡ በላሞቻቸውም ፡ በአህዮቻቸውም ፡
ፋንታ ፡ እህልን ፡ ሰጣቸው ፤ በዚያች ፡ ዓመትም ፡
ስለ ፡ ከብቶቻቸው ፡ ሁሉ ፡ ፋንታ ፡ እህልን ፡
፲፰ መገባቸው ። ዓመቱም ፡ ተፈጸመ ፤ በሁለተኛ
ውም ፡ ዓመት ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጥተው ፡ እን
ዲህ ፡ አሉት ፦ እኛ ፡ ከጌታችን ፡ አንሰውርም ፤
ብሩ ፡ በፍጹም ፡ አለቀ ፥ ከብታችንም ፡ ከጌታ
ችን ፡ ጋር ፡ ነው ፤ ከሰውነታችንና ፡ ከምድራችን ፡
በቀር ፡ በጌታችን ፡ ፊት ፡ አንዳች ፡ የቀረ ፡ የለም ፤
፲፱ እኛ ፡ በፊትህ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እንሞታለን ? ምድ
ራችንስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትጠፋለች ? እኛንም ፡
ምድራችንንም ፡ በእህል ፡ ግዛን ፥ እኛም ፡ ለፈር
ዖን ፡ ባሪያዎች ፡ እንሁን ፥ ምድራችንም ፡ ለእ

ርሱ ፡ ትሁን ፤ እኛ ፡ እንድንድን ፡ እንዳንሞትም ፡ ምድራችንም ፡ እንዳትጠፋ ፡ ዘር ፡ ስጠን ።

፳ ዮሴፍም ፡ የግብፅን ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ለፈርዖን ፡ ገዛ ፤ የግብፅ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ራብ ፡ ስለ ፡ ጸናባቸው ፡ ርስታቸውን ፡ ሸጠዋልና ፤ ምድሪቱ ፡ ለፈርዖን ፡ ሆነች ። ፳፩ ሕዝቡንም ፡ ሁሉ ፡ ከግብፅ ፡ ዳርቻ ፡ እንሥቶ ፡ እስከ ፡ ሌላው ፡ ዳርቻዋ ፡ ድረስ ፡ በሪያዎች ፡ አደረጋቸው ። ፳፪ የካህናትን ፡ ምድር ፡ ብቻ ፡ አልገዛም ፤ ከህናቱ ፡ ከፈርዖን ፡ ዘንድ ፡ ድርጎ ፡ ያገኙ ፡ ነበርና ፤ ፈርዖንም ፡ የሰጣቸውን ፡ ድርጎ ፡ ይበሉ ፡ ነበር ፤ ስለዚህም ፡ ምድራቸውን ፡ አልሸጡም ። ፳፫ ዮሴፍም ፡ ሕዝቡን ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ እነሆ ፡ ዛሬ ፡ እናንተንና ፡ ምድራችሁን ፡ ለፈርዖን ፡ ገዝቻችኋለሁ ፤ ዘር ፡ ውሰዱና ፡ ምድሪቱን ፡ ዝሩ ፤ ፳፬ በመከርም ፡ ጊዜ ፡ ፍሬውን ፡ ከአምስት ፡ እጅ ፡ አንዱን ፡ እጅ ፡ ለፈርዖን ፡ ስጡ ፤ አራቱም ፡ እጅ ፡ ለእናንተ ፡ ለራሳችሁ ፤ ለእርሻው ፡ ዘርና ፡ ለእናንተ ፡ ምግብ ፤ ለቤተ ፡ ሰዎቻችሁና ፡ ለሕፃናቶቻችሁም ፡ ሲሳይ ፡ ይሁን ። ፳፭ እነርሱም ፦ አንተ ፡ አዳንኸን ፤ በጌታችን ፡ ፊት ፡ ሞገስን ፡ እናግኝ ፤ ለፈርዖንም ፳፮ ባሪያዎች ፡ እንሆናለን ፡ አሉት ። ዮሴፍም ፡ ለፈርዖን ፡ ከልሆነችው ፡ ከካህናቱ ፡ ምድር ፡ በቀር ፡ አምስተኛው ፡ እጅ ፡ ለፈርዖን ፡ እንዲሆን ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ሕግ ፡ አደረጋት ።

፳፯ እስራኤልም ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ በጌሤም ፡ አገር ፡ ተቀመጠ ፤ ገዙአትም ፤ ረቡ ፤ እጅግም ፡ ፳፰ በዙ ። ያዕቆብም ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ አሥራ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ተቀመጠ ፤ የያዕቆብም ፡ ሙላው ፡ የሕይወቱ ፡ ዘመን ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ፳፱ ነው ። የእስራኤልም ፡ የሞቱ ፡ ቀን ፡ ቀረበ ፤ ልጁን ፡ ዮሴፍንም ፡ ጠርቶ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፦ በፊትህ ፡ ሞገስን ፡ አግኝቼ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እጅህን ፡ ከጭኔ ፡ በታች ፡ አድርግ ፤ በግብፅ ፡ ምድርም ፡ እንዳትቀብረኝ ፡ ምሕረትንና ፡ እውነትን ፡ ፴ አድርግልኝ ፤ ከአባቶቼም ፡ ጋር ፡ በተኛሁ ፡ ጊዜ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ አውጥተህ ፡ ትወስደኛለህ ፤ በመቃብራቸውም ፡ ትቀብረኛለህ ። እርሱም ፦ እንደ ፡ ቃልህ ፡ አደርጋለሁ ፡ አለ ። ፴፩ እርሱም ፦ ማልልኝ ፡ አለው ። ዮሴፍም ፡ ማለለት ፤ እስራኤልም ፡ በአልጋው ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ሰገደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፰ ።

፩ ከዚህም ፡ ነገር ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ እነሆ ፡ አባትህ ፡ ታምሞአል ፡ ብለው ፡ ለዮሴፍ ፡ ነገሩት ፤ እርሱም ፡ ሁለቱን ፡ ልጆቹን ፡ ምናሴንና ፡ ኤፍ ፪ ሬምን ፡ ይዞ ፡ ሄደ ። ለያዕቆብም ፦ እነሆ ፡ ልጅህ ፡ ዮሴፍ ፡ መጥቶልሃል ፡ ብለው ፡ ነገሩት ፤ እስራኤልም ፡ ተጠነከከረ ፤ በአልጋውም ፡ ላይ ፡ ፫ ተቀመጠ ። ያዕቆብ ፡ ዮሴፍን ፡ አለው ፦ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ አምላክ ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ፬ በሎዛ ፡ ተገለጠልኝ ፤ ባረከኝም ፡ እንዲህም ፡ አለኝ ፦ እነሆ ፡ ፍሬያማ ፡ አደርግሃለሁ ፤ አበዛሃለሁም ፤ ለብዙም ፡ ሕዝብ ፡ ጉባኤ ፡ አደርግሃለሁ ፤ ይህችንም ፡ ምድር ፡ ከአንተ ፡ በኋላ ፡ ለዘላለም ፡ ርስት ፡ ለዘርህ ፡ እሰጣታለሁ ። ፭ አሁንም ፡ እኔ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ከመምጣቴ ፡ በፊት ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ የተወለዱልህ ፡ ሁለቱ ፡ ልጆችህ ፡ ለእኔ ፡ ይሁኑ ፤ ኤፍሬምና ፡ ምናሴ ፡ ለእኔ ፡ እንደ ፡ ሮቤልና ፡ እንደ ፡ ስምዖን ፡ ናቸው ። ፮ ከእነርሱም ፡ በኋላ ፡ የምትወልዳቸው ፡ ልጆች ፡ ለአንተ ፡ ይሁኑ ፤ በርስታቸው ፡ በወንድሞቻቸው ፡ ስም ፡ ይጠሩ ። ፯ እኔም ፡ ከመስጴጦምያ ፡ በመጣሁ ፡ ጊዜ ፤ ወደ ፡ ኤፍራታ ፡ ለመግባት ፡ ጥቂት ፡ ቀርቶኝ ፡ በመንገድ ፡ ሳለሁ ፤ ራሔል ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ሞተችብኝ ፤ በዚያም ፡ በኤፍራታ ፡ መንገድ ፡ ላይ ፤ እርስዋም ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፡ ናት ፤ ቀበርኋት ።

፰ እስራኤልም ፡ የዮሴፍን ፡ ልጆች ፡ አይቶ ፦ ፱ እነዚህ ፡ እነማን ፡ ናቸው ? አለው ። ዮሴፍም ፡ ለአባቱ ፦ እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡ የሰጠኝ ፡ ልጆቼ ፡ ናቸው ፡ አለ ። እርሱም ፦ አባርካቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደዚህ ፡ አቅርብልኝ ፡ አለ ። ፲ የእስራኤልም ፡ ዓይኖች ፡ ከሽምግልና ፡ የተነሣ ፡ ከብደው ፡ ነበር ፤ ማየትም ፡ አይችልም ፡ ነበር ፤ ወደ ፡ እርሱም ፡ አቀረባቸው ፤ ሳማቸውም ፤ ፲፩ አቀፋቸውም ። እስራኤልም ፡ ዮሴፍን ፦ ፊትህን ፡ አያለሁ ፡ ብዬ ፡ አላሰብሁም ፡ ነበር ፤ እነሆም ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘርህን ፡ ደግሞ ፡ አሳ ፲፪ የኝ ፡ አለው ። ዮሴፍም ፡ ከጕልበቱ ፡ ፈቀቅ ፡ አደረጋቸው ፤ ወደ ፡ ምድርም ፡ በግምባሩ ፡ ፲፫ ሰገደ ። ዮሴፍም ፡ ሁለቱን ፡ ልጆቹን ፡ ወሰደ ፤ ኤፍሬምንም ፡ በቀኙ ፡ በእስራኤል ፡ ግራ ፤ ምናሴንም ፡ በግራው ፡ በእስራኤል ፡ ቀኝ ፡ አደረ ፲፬ ገው ፤ ወደ ፡ እርሱም ፡ አቀረባቸው ። እስራኤልም ፡ ቀኝ ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡ በኤፍሬም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ አኖረው ፤ እርሱም ፡ ታናሽ ፡ ነበረ ፤ ግራውንም ፡ በምናሴ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ አኖረ ፤ እጆቹንም ፡ አስተላለፈ ፤ ምናሴ ፡ በኵር ፡ ነበ ፲፭ ርና ። ያዕቆብም ፡ ዮሴፍን ፡ ባረከ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦ አባቶቼ ፡ አብርሃምና ፡ ይስሐቅ ፡ በፊቱ ፡ የሄዱለት ፡ እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፤ ከታናሽነቴ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እኔን ፡ የመገበኝ ፡ ፲፮ እግዚአብሔር ፤ ከክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ያዳነኝ ፡ መልአክ ፤ እርሱ ፡ እነዚህን ፡ ብላቴኖች ፡ ይባርክ ፤ ስሜም ፡ የአባቶቼ ፡ የአብርሃምና ፡ የይስሐቅም ፡ ስም ፡ በእነርሱ ፡ ይጠራ ፤ በምድርም ፡ ፲፯ መካከል ፡ ይብዙ ። ዮሴፍም ፡ አባቱ ፡ ቀኝ ፡ እጁን ፡ በኤፍሬም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ጭኖ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ አሳዘነው ፤ የአባቱንም ፡ እጅ ፡ በምናሴ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይጭነው ፡ ዘንድ ፡ ከኤፍሬም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ፲፰ አነሣው ። ዮሴፍም ፡ አባቱን ፦ አባቴ ፡ ሆይ ፡ እንዲህ ፡ አይደለም ፤ በኵሩ ፡ ይህ ፡ ነውና ፤ ፲፱ ቀኝህን ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ አድርግ ፡ አለው ። አባቱም ፡ እንቢ ፡ አለ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፦ አወቅሁ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፤ አወቅሁ ፤ ይህም ፡ ደግሞ ፡ ሕዝብ ፡

ይሆናል ፡ ታላቅም ፡ ይሆናል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ታናሽ ፡ ወንድሙ ፡ ከእርሱ ፡ ይበልጣል ፥ ዘሩም ፡ የአሕዛብ ፡ ሙላት ፡ ይሆናል ። ፳ ፡ በዚያም ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ባረካቸው ፡— በእናንተ ፡ እስራኤል ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ይባርካል ፡— እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ኤፍሬምና ፡ እንደ ፡ ምናሴ ፡ ያድርግህ ። ኤፍሬምንም ፡ ከምናሴ ፡ ፊት ፡ አደረገው ። ፳፩ ፡ እስራኤልም ፡ ዮሴፍን ፡— እነሆ ፡ እኔ ፡ እሞታለሁ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይሆናል ፥ ወደ ፡ አባቶቻችሁም ፡ ምድር ፡ ይመልሳችኋል ፤ ፳፪ ፡ እኔም ፡ ከአሞራውያን ፡ በሰይፌና ፡ በቀስቴ ፡ የወሰድሁትን ፡ ለአንተ ፡ ከወንድሞችህ ፡ አንድ ፡ እጅ ፡ አብልጬ ፡ ሰጠሁህ ፡ አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፱ ።

፩ ፡ ያዕቆብም ፡ ልጆቹን ፡ ጠርቶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ የሚያገኛችሁን ፡ እንድነግራችሁ ፡ ተሰብሰቡ ።

፪ ፡ እናንተ ፡ የያዕቆብ ፡ ልጆች ፡ ተሰብሰቡ ፥ ስሙም ፤
አባታችሁ ፡ እስራኤልንም ፡ አድምጡ ።

፫ ፡ ሮቤል ፥ አንተ ፡ በኵር ፡ ልጄና ፡ ኃይሌ ፥
የጕብዝናዬም ፡ መጀመሪያ ፡ ነህ ፤
የክብር ፡ አለቃና ፡ የኃይል ፡ አለቃ ።

፬ ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ የምትዋልል ፡ ነህ ፤ አለቅነት ፡ ለአንተ ፡ አይሁን ፤
ወደ ፡ አባትህ ፡ መኝታ ፡ ወጥተሃልና ፤
አረከስኸውም ፤ ወደ ፡ አልጋዬም ፡ ወጣ ።

፭ ፡ ስምዖንና ፡ ሌዊ ፡ ወንድማማች ፡ ናቸው ፤
ሰይፎቻቸው ፡ የዓመፃ ፡ መሣሪያ ፡ ናቸው ።

፮ ፡ በምክራቸው ፥ ነፍሴ ፥ አትግባ ፤
ከጉባኤአቸውም ፡ ጋር ፥ ክብሬ ፥ አትተባበር ፤
በቍጣቸው ፡ ሰውን ፡ ገድለዋልና ፥
በገዛ ፡ ፈቃዳቸውም ፡ በሬን ፡ አስነከሰዋልና ።

፯ ፡ ቍጣቸው ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፥ ጽኑ ፡ ነበርና ፤
ኵርፍታቸውም ፥ ብርቱ ፡ ነበርና ፤
በያዕቆብ ፡ እከፋፍላቸዋለሁ ፥ በእስራኤልም ፡ እበታትናቸዋለሁ ።

፰ ፡ ይሁዳ ፥ ወንድሞችህ ፡ አንተን ፡ ያመሰግኑሃል ፤
እጅህ ፡ በጠላቶችህ ፡ ደንደስ ፡ ላይ ፡ ነው ፤
የአባትህ ፡ ልጆች ፡ በፊትህ ፡ ይሰግዳሉ ።

፱ ፡ ይሁዳ ፡ የአንበሳ ፡ ደቦል ፡ ነው ፤
ልጄ ፡ ሆይ ፥ ከአደንህ ፡ ወጣህ ፤
እንደ ፡ አንበሳ ፡ አሸመቀ ፥ እንደ ፡ ሴት ፡ አንበሳም ፡ አደባ ፤
ያስነሣውስ ፡ ዘንድ ፡ ማን ፡ ይችላል ?

፲ ፡ በትረ ፡ መንግሥት ፡ ከይሁዳ ፡ አይጠፋም ፥
የገዥም ፡ ዘንግ ፡ ከእግሮቹ ፡ መካከል ፥
ገዥ ፡ የሆነው ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፤
የአሕዛብ ፡ መታዘዝም ፡ ለእርሱ ፡ ይሆናል ።

፲፩ ፡ ውርንጫውን ፡ በወይን ፡ ግንድ ፡ ያስራል ፥
የአህያይቱንም ፡ ግልገል ፡ በወይን ፡ አረግ ፤
ልብሱን ፡ በወይን ፡ ያጥባል ፥
መጐናጸፊያውንም ፡ በወይን ፡ ደም ።

፲፪ ፡ ዓይኑም ፡ ከወይን ፡ ይቀላል ፤
ጥርሱም ፡ ከወተት ፡ ነጭ ፡ ይሆናል ።

፲፫ ፡ ዛብሎን ፡ በባሕር ፡ ዳር ፡ ይቀመጣል ፤
እርሱም ፡ ለመርከቦች ፡ ወደብ ፡ ይሆናል ፤
ዳርቻውም ፡ እስከ ፡ ሲዶና ፡ ድረስ ፡ ነው ።

፲፬ ፡ ይሳኮር ፡ አጥንተ ፡ ብርቱ ፡ አህያ ፡ ነው ፥
በበጎች ፡ ጕረኖም ፡ መካከል ፡ ያርፋል ።

፲፭ ፡ ዕረፍትም ፡ መልካም ፡ መሆንዋን ፡ አየ ፥
ምድሪቱም ፡ የለማች ፡ መሆንዋን ፤
ትከሻውን ፡ ለመሸከም ፡ ዝቅ ፡ አደረገ ፥
በሥራም ፡ ገባሬ ፡ ሆነ ።

፲፮ ፡ ዳን ፡ በወገኑ ፡ ይፈርዳል ፥
ከእስራኤል ፡ ነገድ ፡ እንደ ፡ አንዱ ።

፲፯ ፡ ዳን ፡ በጐዳና ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ እባብ ፡ ይሆናል ፥
በመንገድም ፡ እንደ ፡ ቀንዳም ፡ እባብ ፤
ፈረሱን ፡ ከሰኰናው ፡ ይነክሳል ፥
ፈረሰኛም ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ ይወድቃል ።

፲፰ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ መድኃኒትህን ፡ እጠብቃለሁ ።

፲፱ ፡ ጋድን ፡ ዘማቾች ፡ ይዘምቱበታል ፤
እርሱ ፡ ግን ፡ ተከታትሎ ፡ ይዘምትባቸዋል ።

፳ ፡ የአሴር ፡ እንጀራው ፡ ወፍራም ፡ ነው ፥
ለነገሥታቱም ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ መብልን ፡ ይሰጣል ።

፳፩ ፡ ንፍታሌም ፡ የተፈታ ፡ ሚዳቋ ፡ ነው ፤
መልካም ፡ ቃልን ፡ ይሰጣል ።

፳፪ ፡ ዮሴፍ ፡ ትንሹ ፡ የፍሬ ፡ ዛፍ ፡ ነው ፥
በምንጭ ፡ አጠገብ ፡ የሚያፈራ ፡ የፍሬ ፡ ዛፍ ፤
አረጎቹ ፡ በቅጥር ፡ ላይ ፡ ያድጋሉ ።

፳፫ ፡ ቀስተኞች ፡ አስቸገሩት ፥
ነደፉትም ፥ ተቃወሙትም ፤

፳፬ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ቀስቱ ፡ እንደ ፡ ጸና ፡ ቀረ ፤
የእጆቹም ፡ ክንድ ፡ በያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ እጅ ፡ በረታ ፥
በዚያው ፡ በጠባቂው ፡ በእስራኤል ፡ ዓምድ ፥

፳፭ ፡ በአባትህ ፡ አምላክ ፡ እርሱም ፡ የሚረዳህ ፥
ሁሉንም ፡ በሚችል ፡ አምላክ ፡ እርሱም ፡ የሚባርክህ ፥
በሰማይ ፡ በረከት ፡ ከላይ ፡ በሚገኝ ፥
በጥልቅም ፡ በረከት ፡ ከታች ፡ በሚሠራጭ ፥
በጡትና ፡ በማኅፀን ፡ በረከት ።

፳፮ ፡ የአባትህ ፡ በረከቶች ፡
ጽኑዓን ፡ ከሆኑ ፡ ከተራሮች ፡ በረከቶች ፡ ይልቅ ፡ ኃያላን ፡ ናቸው ፤
ዘላለማውያን ፡ ከሆኑ ፡ ከኮረብቶችም ፡ በረከቶች ፡ ይልቅ ፡ ኃያላን ፡ ናቸው ፤
እነርሱም ፡ በዮሴፍ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይሆናሉ ፥
በወንድሞቹ ፡ መካከል ፡ አለቃ ፡ በሆነው ፡ ራስ ፡ አናት ፡ ላይ ።

፳፯ ፡ ብንያም ፡ ነጣቂ ፡ ተኵላ ፡ ነው ፤
የበዘበዘውን ፡ በጥዋት ፡ ይበላል ፥
የማረከውንም ፡ በማታ ፡ ይከፋፍላል ።

፳፰ ፡ እነዚህም ፡ ሁሉ ፡ አሥራ ፡ ሁለቱ ፡ የእስራኤል ፡ ነገዶች ፤ ናቸው ፤ አባታቸው ፡ የነገራቸው ፡

ይህ ፡ ነው ፡ ÷ ባረከቸውም ፤ እያንዳንዳቸውን ፡ እ ፡ ፡ ፡ በረከታቸው ፡ ባረካቸው ። ፳፱ እንዲህ ፡ ብሎም ፡ አዘዛቸው ፡— እኔ ፡ ወደ ፡ ወገኖቼ ፡ እሰ በሰባለሁ ፤ በኬጢያዊ ፡ በኤፍሮን ፡ እርሻ ፡ ላይ ፡ ባለችው ፡ ዋሻ ፡ ከአባቶቼ ፡ ጋር ፡ ቅበሩኝ ፤ ፴ እርስዋም ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ በመምሬ ፡ ፊት ፡ ያለች ÷ አብርሃም ፡ ለመቃብር ፡ ርስት ፡ ከኬጢ ያዊ ፡ ከኤፍሮን ፡ ከእርሻው ፡ ጋር ፡ የገዛት ÷ ፴፩ በለ ፡ ድርብ ፡ ክፍል ፡ ዋሻ ፡ ናት ። አብርሃምና ፡ ሚስቱ ፡ ሣራ ፡ ከዚያ ፡ ተቀበሩ ፤ ይስሐቅና ፡ ሚስቱ ፡ ርብቃ ፡ ከዚያ ፡ ተቀበሩ ፤ ከዚያም ፡ ፴፪ እኔ ፡ ልያን ፡ ቀበርኋት ፤ እርሻውና ፡ በእርስዋ ፡ ላይ ፡ ያለችው ፡ ዋሻ ፡ ከኬጢ ፡ ልጆች ፡ የተገዙ ፡ ፴፫ ናቸው ። ያዕቆብም ፡ ትእዛዙን ፡ ለልጆቹ ፡ ተና ግሮ ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ እግሮቹን ፡ በአልጋው ፡ ላይ ፡ ሰብስበ ፡ ሞተ ÷ ወደ ፡ ወገኖቹም ፡ ተከ ማቸ ።

## ምዕራፍ ፡ ፶ ።

፩ ዮሴፍም ፡ በአባቱ ፡ ፊት ፡ ወደቀ ÷ በእር ፪ ሱም ፡ ላይ ፡ አለቀሰ ÷ ሳመውም ። ዮሴፍም ፡ ባለ ፡ መድኃኒቶች ፡ አገልጋዮቹ ፡ አባቱን ፡ በሽቱ ፡ ያሹት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ ባለ ፡ መድኃኒቶችም ፡ ፫ እስራኤልን ፡ በሽቱ ፡ አሹት ። አርባ ፡ ቀንም ፡ ፈጸሙለት ፤ የሽቱ ፡ መደረጊያው ፡ ወራት ፡ እንደዚሁ ፡ ይፈጸማልና ፤ የግብፅም ፡ ሰዎች ፡ ሰባ ፡ ቀን ፡ አለቀሱለት ።

፬ የልቅሶውም ፡ ወራት ፡ ባለፈ ፡ ጊዜ ፡ ዮሴፍ ፡ ለፈርዖን ፡ ቤተ ፡ ሰቦች ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተና ገረ ፡— እኔ ፡ በፊታችሁ ፡ ሞገስን ፡ አግኝቼ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ለፈርዖን ፡ እንዲህ ፡ ብላችሁ ፡ ፭ ንገሩት ፡— አባቴ ፡ አምሎኛል ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡— እነሆ ፡ እኔ ፡ እሞታለሁ ፤ በቈፈርሁት ፡ መቃ ብር ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ከዚያ ፡ ቅበረኝ ። አሁ ንም ፡ ወጥቼ ፡ አባቴን ፡ ልቅበርና ፡ ልመለስ ። ፮ ፈርዖንም ፡— ውጣ ÷ አባትህንም ፡ እንዳማለህ ፡ ፯ ቅበረው ፡ አለው ። ዮሴፍም ፡ አባቱን ፡ ሊቀ ብር ፡ ወጣ ፤ የፈርዖን ፡ ሎላልትም ፡ ሁሉ ፡ ከእ ርሱ ፡ ጋር ፡ ወጡ ÷ የቤቱ ፡ ሽማግሌዎችም ፡ የግ ፰ ብፅ ፡ ምድር ፡ ሽማግሌዎችም ፡ ሁሉ ፤ የዮሴ ፍም ፡ ቤተ ፡ ሰቦች ፡ ሁሉ ፡ ወንድሞቹም ፡ የአ ባቱም ፡ ቤተ ፡ ሰቦች ፡ ወጡ ፤ ልጆቻቸውንና ፡ በጎቻቸውን ፡ ከብቶቻቸውን ፡ ብቻ ፡ በጌሤም ፡ ፱ ተዉ ። ሰረገሎችም ፡ ፈረሰኞችም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ፲ ወጡ ÷ ሠራዊቱም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነበረ ። በዮ ርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ወዳለችው ፡ ወደ ፡ አጣድ ፡ አው ድማ ፡ መጡ ÷ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ በሆነ ፡ በጽኑ ፡ ልቅሶም ፡ አለቀሱለት ፤ ለአባቱም ሰባት ፡ ቀን ፡ ፲፩ ልቅሶ ፡ አደረገለት ። በዚያች ፡ ምድር ፡ የሚ ኖሩ ፡ የከነዓን ፡ ሰዎችም ፡ በአጣድ ፡ አውድማ ፡ የሆነውን ፡ ልቅሶ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡— ይህ ፡ ለግብፅ ፡ ሰዎች ፡ ታላቅ ፡ ልቅሶ ፡ ነው ፡ አሉ ፤ ስለዚህም ፡ የዚያን ፡ ቦታ ፡ ስም ፡ አቤል ፡ ምጽራይም ፡ ብለው ፡ ጠሩት ፤ እርሱም ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ፲፪ ነው ። ልጆቹም ፡ እንዳዘዛቸው ፡ እንደዚያው ፡ ፲፫ አደረጉለት ፤ ልጆቹም ፡ ወደ ፡ ከነዓን ፡ ምድር ፡ አጓዙት ÷ ባለ ፡ ሁለት ፡ ክፍል ፡ በሆነች ፡ ዋሻም ፡ ቀበሩት ፤ እርስዋም ፡ በመምሬ ፡ ፊት ፡ ያለች ÷ አብርሃም ፡ ለመቃብር ፡ ርስት ፡ ከኬጢያዊ ፡ ከኤፍሮን ፡ ከእርሻው ፡ ጋር ፡ የገዛት ፡ ዋሻ ፡ ናት ። ፲፬ ዮሴፍና ፡ ወንድሞቹ ፡ አባቱንም ፡ ሊቀብሩ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የወጡት ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ አባ ቱን ፡ ከቀበረ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ተመለሱ ።

፲፭ የዮሴፍም ፡ ወንድሞች ፡ አባታቸው ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ አሉ ፡— ምናልባት ፡ ዮሴፍ ፡ ይጠላን ፡ ይሆናል ÷ ባደረግንበትም ፡ ክፋት ፡ ሁሉ ፡ ብድራት ፡ ይመልስብን ፡ ይሆ ፲፮ ናል ። ወደ ፡ ዮሴፍም ፡ መልእክት ፡ ላኩ ፡ እንዲ ህም ፡ አሉት ፡— አባትህ ፡ ገና ፡ ሳይሞት ፡ እን ፲፯ ዲህ ፡ ብሎ ፡ አዝዞአል ፡— ዮሴፍን ፡ እንዲህ ፡ በሉት ፡— እባክህ ፡ የወንድሞችህን ፡ በደል ፡ ኃጢአታቸውንም ፡ ይቅር ፡ በል ÷ እነርሱ ፡ በአ ንተ ፡ ክፍተውብሃልና ፤ አሁንም ፡ እባክህ ፡ የአ ባትህ ፡ አምላክ ፡ ባሪያዎች ፡ የበደሉህን ፡ ይቅር ፡ ፲፰ በል ። ዮሴፍም ፡ ይህን ፡ ሲሉት ፡ አለቀሰ ። ወን ድሞቹ ፡ ደግሞ ፡ መጡ ፡ በፊቱም ፡ ሰግደው ፡— እነሆ ፡ እኛ ፡ ለአንተ ፡ ባሪያዎችህ ፡ ነን ፡ አሉት ። ፲፱ ዮሴፍም ፡ አላቸው ፡— አትፍሩ ፤ እኔ ፡ በእግዚአ ፳ ብሔር ፡ ፋንታ ፡ ነኝን ? እናንተ ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ አሰባችሁብኝ ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡ ሆነው ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ እንዲድን ፡ ለማድረግ ፡ ፳፩ ለመልካም ፡ አሰበው ። አሁንም ፡ አትፍሩ ፤ እኔ ፡ እናንተንና ፡ ልጆቻችሁን ፡ እመግባችኋለሁ ። አጽናናቸውም ፡ ደስ ፡ አሰኛቸውም ።

፳፪ ዮሴፍም ፡ በግብፅ ፡ ተቀመጠ ÷ እርሱና ፡ የአ ባቱም ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፤ ዮሴፍም ፡ መቶ ፡ አሥር ፡ ፳፫ ዓመት ፡ ኖረ ። ዮሴፍም ፡ የኤፍሬምን ፡ ልጆች ፡ እስከ ፡ ሦስት ፡ ትውልድ ፡ አየ ፤ የምናሴ ፡ ልጅ ፡ የማኪር ፡ ልጆችም ፡ በዮሴፍ ፡ ጭን ፡ ላይ ፡ ፳፬ ተወለዱ ። ዮሴፍም ፡ ወንድሞቹን ፡ አለ ፡— እኔ ፡ እሞታለሁ ፤ እግዚአብሔርም ፡ መጐብኘትን ፡ ይጐበኛችኋል ÷ ከዚህችም ፡ ምድር ፡ ያወጣች ኋል ፤ ለአብርሃምና ፡ ለይስሐቅ ፡ ለያዕቆብም ፡ ፳፭ ወደ ፡ ማለላቸው ፡ ምድር ፡ ያደርሳችኋል ። ዮሴ ፍም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡— እግዚአብሔር ፡ ሲያስባችሁ ፡ አጥንቴን ፡ ከዚህ ፡ አንሥታችሁ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ውሰዱ ፡ ብሎ ፡ አማላቸው ። ፳፮ ዮሴፍም ፡ በመቶ ፡ አሥር ፡ ዓመት ፡ ዕድሜው ፡ ሞተ ፤ በሽቱም ፡ አሹት ÷ በግብፅ ፡ ምድር ፡ በሣ ጥን ፡ ውስጥ ፡ አኖሩት ።

• • •

# ኦሪት ፡ ዘጸአት ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ ከያዕቆብ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ የገቡት ፡ የእ
ስራኤል ፡ ልጆች ፡ ስሞች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤
፪ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከቤተ ፡ ሰቡ ፡ ጋር ፡ ገባ ። ሮቤል ÷
፫ ስምዖን ÷ ሌዊ ÷ ይሁዳ ÷ ይሳኮር ÷ ዛብሎን ÷
፬ ብንያም ÷ ዳን ÷ ንፍታሌም ÷ ጋድ ÷ አሴር ።
፭ ከያዕቆብ ፡ ጒልበት ፡ የወጡት ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
ሰባ ፡ ነፍሶች ፡ ነበሩ ፤ ዮሴፍም ፡ አስቀድሞ ፡
፮ በግብፅ ፡ ነበረ ። ዮሴፍም ፡ ሞተ ÷ ወንድሞ
፯ ቹም ÷ ያም ፡ ትውልድ ፡ ሁሉ ። የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ አፈሩ ÷ እጅግም ፡ በዙ ÷ ተባዙም ÷
እጅግም ፡ ጸኑ ፤ ምድሪቱም ፡ በእነርሱ ፡ ሞላች ።
፰ በግብፅም ፡ ዮሴፍን ፡ ያላወቀ ፡ አዲስ ፡ ንጉሥ ፡
፱ ተነሣ ። እርሱም ፡ ሕዝቡን ፡ —እነሆ ÷ የእስ
ራኤል ፡ ልጆች ፡ ሕዝብ ፡ ከእኛ ፡ ይልቅ ፡ በዝ
፲ ተዋል ፡ በርትተውማል ፤ እንዳይበዙ ÷ ሰል
ፍም ፡ በተነሣብን ፡ ጊዜ ፡ ጠላቶቻችንን ፡ እግ
ዘው ፡ እንዳይወጉን ፡ ከምድሪቱም ፡ እንዳይ
፲፩ ወጡ ÷ኑ ፡ እንጠበብባቸው ፡ አለ ። በብርቱ ፡
ሥራም ፡ ያስጨንቁአቸው ፡ ዘንድ ፡ ግብር ፡ አስገ
ባሪዎችን ፡ ሾመባቸው ፤ ለፈርዖንም ፡ ፊቶም
ንና ፡ ራምሴን ፡ ጽኑ ፡ ከተሞች ፡ አድርገው ፡
፲፪ ሠሩ ። ነገር ፡ ግን ፡ እንዳስጨነቁአቸው ፡ መጠን ፡
እንዲሁ ፡ በዙ ÷ እጅግም ፡ ጸኑ ፤ ከእስራኤልም ፡
፲፫ ልጆች ፡ የተነሣ ፡ ተጸይፈዋቸው ፡ ነበር ። ግብፃ
ውያንም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ በመከራ ፡
፲፬ ገዙአቸው ። በጽኑ ፡ ሥራ ÷ በጭቃ ፡ በጡብም ፡
በእርሻም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ÷ በመከራም ፡ በሚያሠ
ሩአቸው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ÷ ሕይወታቸውን ፡ ያስ
መርሩአቸው ፡ ነበር ።
፲፭ የግብፅም ፡ ንጉሥ ፡ አንዲቱ ፡ ሲፓራ ፡ ሁለ
ተኛይቱም ፡ ፉሐ ፡ የሚባሉትን ፡ የዕብራውያ
፲፮ ንን ፡ አዋላጆች ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ፡— እና
ንተ ፡ የዕብራውያንን ፡ ሴቶች ፡ ስታዋልዱ ÷
ለመውለድ ፡ እንደ ፡ ደረሱ ፡ ባያችሁ ፡ ጊዜ ÷
ወንድ ፡ ቢሆን ፡ ግደሉት ፤ ሴት ፡ ብትሆን ፡ ግን ፡
፲፯ በሕይወት ፡ ትኑር ። አዋላጆች ፡ ግን ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ ፈሩ ÷ የግብፅ ፡ ንጉሥም ፡ እንዳዘ
ዛቸው ፡ አላደረጉም ÷ ወንዶቹን ፡ ሕፃናትንም ፡
፲፰ አዳኑአቸው ። የግብፅም ፡ ንጉሥ ፡ አዋላጆ
ችን ፡ ጠርቶ ፡ —ለምን ፡ እንዲህ ፡ አደረጋችሁ ?
ወንዶቹን ፡ ሕፃናትንስ ፡ ለምን ፡ አዳናችሁ ?
፲፱ አላቸው ። አዋላጆችም ፡ ፈርዖንን ፡ —የዕብራው
ያን ፡ ሴቶች ፡ እንደ ፡ ግብፅ ፡ ሴቶች ፡ ስላልሆኑ ፤
እነርሱ ፡ ጠንካሮች ፡ ናቸውና ፡ አዋላጆች ፡ ሳይ
፳ ገቡ ፡ ስለሚወልዱ ፡ ነው ፡ አሉት ። እግዚአ
ብሔርም ፡ ለአዋላጆች ፡ መልካም ፡ አደረገላ
፳፩ ቸው ፤ ሕዝቡም ፡ በዛ ÷ እጅግም ፡ ጸና ። እን
ዲህም ፡ ሆነ ፤ አዋላጆች ፡ እግዚአብሔርን ፡
፳፪ ስለ ፡ ፈሩ ፡ ቤቶችን ፡ አደረገላቸው ። ፈርዖ
ንም ፡ —የሚወለደውን ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ ወንዝ ፡ ጣሉት ÷ ሴትን ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡
ግን ፡ በሕይወት ፡ አድኑአት ፡ ብሎ ፡ ሕዝቡን ፡
ሁሉ ፡ አዘዘ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ከሌዊ ፡ ወገንም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሄዶ ፡ የሌ
፪ ዊን ፡ ልጅ ፡ አገባ ። ሴቲቱም ፡ ፀነሰች ÷ ወንድ ፡
ልጅም ፡ ወለደች ፤ መልካምም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
፫ ባየች ፡ ጊዜ ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ ሸሸገችው ። ደግ
ሞም ፡ ልትሸሽገው ፡ ባልቻለች ፡ ጊዜ ÷ የደን
ገል ፡ ሣጥን ፡ ለእርሱ ፡ ወስዳ ፡ ዝፍትና ፡ ቅጥ
ራን ፡ ለቀለቀችው ፤ ሕፃኑንም ፡ አኖረችበት ÷
በወንዝም ፡ ዳር ፡ ባለ ፡ በቄጠማ ፡ ውስጥ ፡ አስ
፬ ቀመጠችው ። እኅቱም ፡ የሚደረግበትን ፡
ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ በሩቅ ፡ ቆማ ፡ ትጐበኘው ፡
፭ ነበር ። የፈርዖንም ፡ ልጅ ፡ ልትታጠብ ፡ ወደ ፡
ወንዝ ፡ ወረደች ፤ ደንገጥሮችዋም ፡ በወንዝ ፡
ዳር ፡ ይሄዱ ፡ ነበር ፤ ሣጥኑንም ፡ በቄጠማ ፡
ውስጥ ፡ አየች ÷ ደንገጥርዋንም ፡ ልካ ፡ አስመ
፮ ጣችው ። በከፈተችውም ፡ ጊዜ ፡ ሕፃኑን ፡
አየች ÷ እነሆም ፡ ሕፃኑ ፡ ያለቅስ ፡ ነበር ፤ እዘን
ችለትም ፡— ይህ ፡ ከዕብራውያን ፡ ልጆች ፡
፯ አንድ ፡ ነው ፡ አለች ። እኅቱም ፡ ለፈርዖን ፡
ልጅ ፡— ሕፃኑን ፡ ታጠባልሽ ፡ ዘንድ ፡ ሄጄ ፡
የምታጠባ ፡ ሴት ፡ ከዕብራውያን ፡ ሴቶች ፡ ልጥ
፰ ራልሽን ? አለቻት ። የፈርዖንም ፡ ልጅ ፡—
ሂጂ ፡ አለቻት ፤ ብላቴናይቱም ፡ ሄዳ ፡ የሕፃኑን ፡
፱ እናት ፡ ጠራች ። የፈርዖንም ፡ ልጅ ፡— ይህን ፡
ሕፃን ፡ ወስደሽ ፡ አጥቢልኝ ÷ ዋጋሽንም ፡ እሰ
ጥሻለሁ ፡ አለቻት ። ሴቲቱም ፡ ሕፃኑን ፡ ወስዳ ፡
፲ አጠባችው ። ሕፃኑም ፡ አደገ ÷ ወደ ፡ ፈርዖ
ንም ፡ ልጅ ፡ ዘንድ ፡ አመጣችው ÷ ለእርስዋም ፡
ልጅ ፡ ሆናት ። እኔ ፡ ከውኃ ፡ አውጥቼዋለ
ሁና ፡ ስትልም ፡ ስሙን ፡ ሙሴ ፡ ብላ ፡ ጠራ
ችው ።
፲፩ በዚያም ፡ ወራት ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ ሙሴ ፡
ጎበዝ ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ወንድሞቹ ፡ ወጣ ÷
የሥራቸውንም ፡ መከራ ፡ ተመለከተ ፤ የግብ
ፅም ፡ ሰው ፡ የወንድሞቹን ፡ የዕብራውያንን ፡
፲፪ ሰው ፡ ሲመታ ፡ አየ ። ወዲህና ፡ ወዲያም ፡
ተመለከተ ÷ ማንንም ፡ አላየም ÷ ግብፃዊው
ንም ፡ ገደለ ÷ በአሸዋም ፡ ውስጥ ፡ ሸሸገው ።
፲፫ በሁለተኛውም ፡ ቀን ፡ ወጣ ÷ ሁለቱም ፡ የዕብራ
ውያን ፡ ሰዎች ፡ ሲጣሉ ፡ አየ ፤ በዳዩንም ፡—
ለምን ፡ ባልንጀራህን ፡ ትመታዋለህ ? አለው ።
፲፬ ያም ፡— በእኛ ፡ ላይ ፡ አንተን ፡ አለቃ ፡ ወይስ ፡
ዳኛ ፡ ማን ፡ አደረገህ ? ወይስ ፡ ግብፃዊውን ፡
እንደ ፡ ገደልኸው ፡ ልትገድለኝ ፡ ትሻለህን ?

አለው ። ሙሴም ፡— በእውነት ፡ ይህ ፡ ነገር ፡
፲፭ ታውቆአል ፡ ብሎ ፡ ፈራ ። ፈርዖንም ፡ ይህን ፡
ነገር ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ሙሴን ፡ ሊገድለው ፡ ፈለገ ።
ሙሴ ፡ ግን ፡ ከፈርዖን ፡ ፊት ፡ ኰበለለ ፣ በም
ድያምም ፡ ምድር ፡ ተቀመጠ ፤ በውኃም ፡ ጕድ
ጓድ ፡ አጠገብ ፡ ዐረፈ ።
፲፮ ለምድያምም ፡ ካህን ፡ ሰባት ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡
ነበሩት ፤ እነርሱም ፡ መጥተው ፡ ውኃ ፡ ቀዱ ፣
የአባታቸውንም ፡ በጎች ፡ ሊያጠጡ ፡ የውኃ
፲፯ ውን ፡ ገንዳ ፡ ሞሉ ። እረኞችም ፡ መጥተው ፡
ገፉአቸው ፤ ሙሴ ፡ ግን ፡ ተነሥቶ ፡ ረዳቸው ፣
፲፰ በጎቻቸውንም ፡ አጠጣላቸው ። ወደ ፡ አባታ
ቸው ፡ ወደ ፡ ራጉኤልም ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡—
ስለ ፡ ምን ፡ ዛሬ ፡ ፈጥናችሁ ፡ መጣችሁ ? አላ
፲፱ ቸው ። እነርሱም ፡— አንድ ፡ የግብፅ ፡ ሰው ፡
ከእረኞች ፡ እጅ ፡ አዳነን ፣ ደግሞም ፡ ቀዳልን ፣
፳ በጎቻችንንም ፡ አጠጣ ፡ አሉ ። ልጆቹንም ፡—
እርሱ ፡ ወዴት ፡ ነው ? ለምንስ ፡ ያንን ፡ ሰው ፡
ተዋችሁት ? ጥሩት ፡ እንጀራም ፡ ይብላ ፡ አላ
፳፩ ቸው ። ሙሴም ፡ ከዚያ ፡ ሰው ፡ ጋር ፡ ሊቀ
መጥ ፡ ወደደ ፤ ልጁንም ፡ ሲፓራን ፡ ለሙሴ ፡
፳፪ ሚስት ፡ ትሆነው ፡ ዘንድ ፡ ሰጠው ። ወንድ ፡
ልጅም ፡ወለደች ፡— በሌላ ፡ ምድር ፡ መጻተኛ ፡
ነኝ ፡ ሲል ፡ ስሙን ፡ ጌርሳም ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።
፳፫ ከዚያም ፡ ከብዙ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤
የግብፅ ፡ ንጉሥ ፡ሞተ ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
ከባርነት ፡ የተነሣ ፡ አለቀሱ ፣ ጮኹም ፣ ስለ ፡
ባርነታቸውም ፡ ጩኸታቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአ
፳፬ ብሔር ፡ ወጣ ። እግዚአብሔርም ፡ የልቅሶአ
ቸውን ፡ድምፅ ፡ሰማ ፣ እግዚአብሔርም ፡ ከአ
ብርሃምና ፡ ከይስሐቅ ፡ ከያዕቆብም ፡ ጋር ፡ ያደ
፳፭ ረገውን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አሰበ ። እግዚአብሔ
ርም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ አየ ፣ እግዚአብ
ሔርም ፡ በእነርሱ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ አወቀ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ሙሴም ፡ የዮቶርን ፡ የአማቱን ፡ የምድያምን ፡
ካህን ፡ በጎች ፡ ይጠብቅ ፡ ነበር ፤ ወደ ፡ ምድረ ፡
በዳ ፡ ዳርቻም ፡ በጎቹን ፡ነዳ ፣ ወደ ፡ እግዚአብሔ
፪ ርም ፡ ተራራ ፡ ወደ ፡ ኮሬብ ፡ መጣ ። የእግዚአ
ብሔርም ፡ መልአክ ፡ በእሳት ፡ ነበልባል ፡ በእ
ሾህ ፡ ቍጥቋጦ ፡ መካከል ፡ ታየው ፤ አየም ፡
ቍጥቋጦው ፡ በእሳት ፡ ሲነድድ ፡ ቍጥቋጦውም ፡
፫ ሳይቃጠል ፡ አየ ። ሙሴም ፡— ልሂድና ፡ ቍጥቋ
ጦው ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አልተቃጠለም ፡ ይህን ፡ ታላቅ ፡
፬ ራእይ ፡ ልይ ፡ አለ ። እግዚአብሔር ፡ እርሱ ፡
ይመለከት ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡
እግዚአብሔር ፡ ከቍጥቋጦው ፡ ውስጥ ፡ እር
ሱን ፡ ጠርቶ ፡— ሙሴ ፣ ሙሴ ፡ ሆይ ፡ አለ ።
፭ እርሱም ፡— እነሆኝ ፡ አለ ። ወደዚህ ፡ አትቅ
ረብ ፤ አንተ ፡ የቆምህበት ፡ስፍራ ፡ የተቀደሰች ፡
መሬት ፡ ናትና ፡ ጫማህን ፡ ከእግርህ ፡ አውጣ ፡
፮ አለው ። ደግሞም ፡— እኔ ፡ የአባትህ ፡ አምላክ ፣
የአብርሃም ፡ አምላክ ፡ የይስሐቅም ፡ አምላክ ፡
የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ ነኝ ፡ አለው ። ሙሴም ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ ፈርቶአ
፯ ልና ፡ ፊቱን ፡ ሸፈነ ። እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡—
በግብፅ ፡ ያለውን ፡ የሕዝቤን ፡ መከራ ፡ በእው
ነት ፡ አየሁ ፣ ከአስገባሪዎቻቸውም ፡ የተነሣ ፡
ጩኸታቸውን ፡ ሰማሁ ፤ ሥቃያቸውንም ፡ አው
፰ ቄአለሁ ፤ ከግብፃውያንም ፡ እጅ ፡ አድናቸው ፡
ዘንድ ፣ ከዚያችም ፡ አገር ፡ ወተትና ፡ ማር ፡
ወደምታፈስሰው ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ሰፊይቱና ፡ ወደ ፡
መልካሚቱ ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ከነዓናውያንም ፡ ወደ ፡
ኬጢያውያንም ፡ ወደ ፡ አሞራውያንም ፡ ወደ ፡
ፌርዛውያንም ፡ ወደ ፡ ኤዊያውያንም ፡ ወደ ፡
ኢያቡሳውያንም ፡ ስፍራ ፡ አወጣቸው ፡ ዘንድ ፡
፱ ወረድሁ ። አሁንም ፡ እነሆ ፡ የእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ጩኸት ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ወጣ ፤ ግብፃውያንም ፡
የሚያደርጉባቸውን ፡ ግፍ ፡ ደግሞ ፡ አየሁ ።
፲ አሁንም ፡ና ፣ ሕዝቤን ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡
ከግብፅ ፡ ታወጣ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ፈርዖን ፡ እልክ
፲፩ ሃለሁ ። ሙሴም ፡ እግዚአብሔርን ፡— ወደ ፡ ፈር
ዖን ፡ የምሄድ ፡ የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ ከግብፅ ፡
፲፪ የማወጣ ፡ እኔ ፡ ማን ፡ ነኝ ? አለው ። እርሱም ፡—
በእውነት ፡ እኔ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ እሆናለሁ ፤
እኔም ፡ እንደ ፡ ላክሁህ ፡ ምልክትህ ፡ ይህ ፡ ነው ፤
ሕዝቡን ፡ ከግብፅ ፡ ባወጣህ ፡ ጊዜ ፡ በዚህ ፡
ተራራ ፡ ላይ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ትገዛላችሁ ፡
አለ ።
፲፫ ሙሴም ፡ እግዚአብሔርን ፡— እነሆ ፣ እኔ ፡ ወደ ፡
እስራኤል ፡ ልጆች ፡ በመጣሁ ፡ ጊዜ ፡— የአባቶ
ቻችሁ ፡ አምላክ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ላከኝ ፡ በል
ሁም ፡ ጊዜ ፡— ስሙስ ፡ ማን ፡ ነው ? ባሉኝ ፡ ጊዜ ፣
፲፬ ምን ፡ እላቸዋለሁ ? አለው ። እግዚአብሔርም ፡
ሙሴን ፡— «ያለና ፡ የሚኖር ፡» እኔ ፡ ነኝ ፡ አለው ፤
እንዲህ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡— «ያለና ፡ የሚ
ኖር ፡» ወደ ፡ እናንተ ፡ ላከኝ ፡ ትላለህ ፡ አለው ።
፲፭ እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡—
ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ትላለህ ፡— የአ
ባቶቻችሁ ፡ አምላክ ፣ የአብርሃም ፡ አምላክ ፡ የይ
ስሐቅም ፡ አምላክ ፡ የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ላከኝ ፤ ይህ ፡ ለዘላ
ለሙ ፡ ስሜ ፡ ነው ፣ እስከ ፡ ልጅ ፡ ልጅ ፡ ድረ
፲፮ ስም ፡ መታሰቢያዬ ፡ ይህ ፡ ነው ። ሂድ ፡ የእስ
ራኤልንም ፡ሽማግሌዎች ፡ሰብስብ ፡—እግዚአብ
ሔር ፡ የአባቶቻችሁ ፡ አምላክ ፡ የአብርሃም ፡
የይስሐቅም ፡ የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡— መጐብኘ
ትን ፡ ጐበኘኋችሁ ፣ በግብፅም ፡ የሚደረግባች
፲፯ ሁን ፡ አየሁ ፤ ከግብፅም ፡ መከራ ፡ ወደ ፡ ከነዓና
ውያን ፡ ወደ ፡ ኬጢያውያንም ፡ ወደ ፡ አሞራ
ውያንም ፡ ወደ ፡ ፌርዛውያንም ፡ ወደ ፡ ኤዊያ
ውያንም ፡ ወደ ፡ ያቡሳውያንም ፡ አገር ፡ ወተ
ትና ፡ ማር ፡ ወደምታፈስስ ፡ አገር ፡ አወጣችኋለሁ ፡
፲፰ አልሁ ፡ ብለው ፡ ተገለጠልኝ ፡ በላቸው ። እነር
ሱም ፡ ቃልህን ፡ ይሰማሉ ፤ አንተና ፡ የእስራ
ኤል ፡ ሽማግሌዎች ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ንጉሥ ፡
ትገቡላችሁ ፡— የዕብራውያን ፡ አምላክ ፡ እግዚ

እግዚአብሔር፡ተገልጦልን፤ አሁንም፡ለአምላካችን፡ለእግዚአብሔር፡እንሠዋ፡ዘንድ፡የሦስት፡ቀን፡መንገድ፡በምድረ፡በዳ፡እንሂድ፡ትሉታላችሁ። ፲፱ ነገር፡ግን፡በጽኑ፡እጅ፡ካልሆነ፡በቀር፡ትሄዱ፡ዘንድ፡የግብፅ፡ንጉሥ፡እንደማይፈቅድላችሁ፡እኔ፡አውቃለሁ። ፳ እኔም፡እጄን፡እዘረጋለሁ፥በማደርግባቸውም፡ተአምራቴ፡ሁሉ፡ግብፅን፡እመታለሁ፤ ከዚያም፡በኋላ፡ይለቅቃችኋል። ፳፩ በግብፃውያንም፡ፊት፡ለዚህ፡ሕዝብ፡ሞገስን፡እሰጣለሁ፤ እንዲህም፡ይሆናል፤ በሄዳችሁ፡ጊዜ፡ባዶ፡እጃችሁን፡አትሄዱም፤ ፳፪ ነገር፡ግን፡እያንዳንዲቱ፡ሴት፡ከጎረቤትዋ፡በቤትዋም፡ከበችው፡ሴት፡የብር፡ዕቃ፡የወርቅ፡ዕቃ፡ልብስም፡ትለምናለች፤ በወንዶችና፡በሴቶች፡ልጆቻችሁ፡ላይ፡ታደርጉታላችሁ፤ ግብፃውያንንም፡ትበዘብዛላችሁ።

## ምዕራፍ፡፬።

፩ ሙሴም፡መለሰ፡— እነሆ፡አያምኑኝም፡ቃሌንም፡አይሰሙም፡— እግዚአብሔር፡ከቶ፡አልተገለጠልህም፡ይሉኛል፡አለ። ፪ እግዚአብሔርም፡— ይህች፡በእጅህ፡ያለችው፡ምንድርናት? አለው። እርሱም፡— በትር፡ናት፡አለ። ፫ ወደ፡መሬት፡ጣላት፡አለው፤ እርሱም፡በመሬት፡ጣላት፥እባብም፡ሆነች፤ ሙሴም፡ከእርሱ፡ሸሸ። ፬፡፭ እግዚአብሔርም፡ሙሴን፡— የአባቶቻቸው፡አምላክ፥የአብርሃም፡አምላክ፡የይስሐቅም፡አምላክ፡የያዕቆብም፡አምላክ፥እግዚአብሔር፡እንደ፡ተገለጠልህ፡እንዲያምኑ፡እጅህን፡ዘርግተህ፡ጅራትዋን፡ያዝ፡አለው። እጁንም፡ዘርግቶ፡ያዛት፡በእጁም፡ውስጥ፡በትር፡ሆነች። ፮ እግዚአብሔርም፡ደግሞ፡— እጅህን፡ወደ፡ብብትህ፡አግባ፡አለው። እጁንም፡ወደ፡ብብቱ፡አገባት፤ በወጣትም፡ጊዜ፡እነሆ፥እጁ፡እንደ፡በረዶ፡ለምጽ፡ሆነች። ፯ እርሱም፡— እጅህን፡ወደ፡ብብትህ፡መልስ፡አለው። እጁንም፡ወደ፡ብብቱ፡መለሳት፥ከብብቱም፡ባወጣት፡ጊዜ፡እነሆ፡ተመልሳ፡ገላውን፡መሰለች። ፰ ደግሞም፡አለው፡— እንዲህም፡ይሆናል፤ ባያምኑህ፡የፊተኛይቱንም፡ምልክት፡ነገር፡ባይሰሙ፥የሁለተኛይቱን፡ምልክት፡ነገር፡ያምናሉ። ፱ እንዲህም፡ይሆናል፤ እነዚህን፡ሁለት፡ምልክቶች፡ባያምኑ፡ቃልህንም፡ባይሰሙ፥ከወንዙ፡ውኃን፡ውሰድ፥በደረቁም፡መሬት፡ላይ፡አፍስሰው፤ ከወንዙም፡የወሰድኸው፡ውኃ፡በደረቁ፡መሬት፡ላይ፡ደም፡ይሆናል። ፲ ሙሴም፡እግዚአብሔርን፡— ጌታ፡ሆይ፥እኔ፡አፈ፡ኰልታፋ፡ምላሴም፡ጸያፍ፡የሆነ፡ሰው፡ነኝ፤ ትናንትና፡ከትናንት፡ወዲያ፡ባሪያህንም፡ከተናገርኸኝ፡ጀምሮ፡አፈ፡ትብ፡ሰው፡አይደለሁም። ፲፩ እግዚአብሔርም፡— የሰውን፡አፍ፡የፈጠረ፡ማን፡ነው? ዲዳስ፡ደንቆሮስ፡የሚያይስ፡ዕውርስ፡ያደረገ፡ማን፡ነው? እኔ፡እግዚአብሔር፡አይደለሁምን? ፲፪ እንግዲህ፡አሁን፡ሂድ፥እኔም፡ከአፍህ፡ጋር፡እሆናለሁ፥የምትናገረውንም፡አስተምርሃለሁ፡አለው። ፲፫ እርሱም፡— ጌታ፡ሆይ፥በምትልከው፡ሰው፡እጅ፡ትልክ፡ዘንድ፡እለምንሃለሁ፡አለ። ፲፬ የእግዚአብሔርም፡ቍጣ፡በሙሴ፡ላይ፡ነደደ፡እንዲህም፡አለ፡— ሌዋዊው፡ወንድምህ፡አሮን፡አለ፡አይደለምን? እርሱ፡ደኅና፡እንዲናገር፡አውቃለሁ፤ እነሆም፡ደግሞ፡ሊገናኝህ፡ይመጣል፤ ባየህም፡ጊዜ፡በልቡ፡ደስ፡ይለዋል። ፲፭ አንተም፡ትናገረዋለህ፡ቃሉንም፡በአፉ፡ታደርገዋለህ፤ እኔ፡ከአፍህና፡ከአፉ፡ጋር፡እሆናለሁ፥የምታደርጉትንም፡አስተምራችኋለሁ። ፲፮ እርሱ፡ስለ፡አንተ፡ከሕዝቡ፡ጋር፡ይናገራል፤ እንዲህም፡ይሆናል፤ እርሱ፡አፍ፡ይሆንልሃል፡አንተም፡በእግዚአብሔር፡ፋንታ፡ትሆንለታለህ። ፲፯ ይህችንም፡ተአምራት፡የምታደርግባትን፡በትር፡በእጅህ፡ያዛት፡ሂድ።

፲፰ ሙሴም፡ሄደ፥ወደ፡አማቱ፡ወደ፡ዮቶር፡ተመለሰ፡— እስከ፡ዛሬ፡በሕይወት፡እንዳሉ፡አይ፡ዘንድ፡ተመልሼ፡ወደ፡ግብፅ፡ወደ፡ወንድሞቼ፡ልሂድ፡አለው። ዮቶርም፡ሙሴን፡— በሰላም፡ሂድ፡አለው። ፲፱ እግዚአብሔርም፡ሙሴን፡በምድያም፡— ነፍስህን፡የሚሹአት፡ሰዎች፡ሁሉ፡ሞተዋልና፡ተመልሰህ፡ወደ፡ግብፅ፡ሂድ፡አለው። ፳ ሙሴም፡ሚስቱንና፡ልጆቹን፡ወሰደ፥በአህያ፡ላይም፡አስቀመጣቸው፥ወደ፡ግብፅም፡አገር፡ተመለሰ፤ ሙሴም፡የእግዚአብሔርን፡በትር፡ይዞ፡ሄደ። ፳፩ እግዚአብሔርም፡ሙሴን፡አለው፡— ወደ፡ግብፅ፡ስትመለስ፡በእጅህ፡ያደረግሁትን፡ተአምራት፡ሁሉ፡በፈርዖን፡ፊት፡ታደርገው፡ዘንድ፡ተመልከት፤ እኔ፡ግን፡ልቡን፡አጸናዋለሁ፥ሕዝቡንም፡አይለቅቅም። ፳፪ ፈርዖንንም፡— እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— እስራኤል፡የበኵር፡ልጄ፡ነው፤ ፳፫ ይገዛልኝ፡ዘንድ፡ልጄን፡ልቀቅ፡አልሁህ፤ አንተም፡ትለቅቀው፡ዘንድ፡እንቢ፡አልህ፤ እነሆ፡እኔ፡የበኵር፡ልጅህን፡እገድላለሁ፡ትለዋለህ።

፳፬ እንዲህም፡ሆነ፤ በመንገድ፡ላይ፡በደረበት፡በፍራ፡እግዚአብሔር፡ተገናኘው፥ሊገድለውም፡ፈለገ። ፳፭ ሲፓራም፡ሚስቱ፡ባልጩት፡ወሰደች፥የልጅዋንም፡ሸለፈት፡ገረዘች፥ወደ፡እግሩም፡ጣለችው፡— አንተ፡ለእኔ፡የደም፡ሙሽራ፡ነህ፡አለች። ፳፮ ከእርሱም፡ፈቀቅ፡አለ። የዚያን፡ጊዜ፡— ስለ፡ግርዛቱ፡አንተ፡የደም፡ሙሽራ፡ነህ፡አለች።

፳፯ እግዚአብሔርም፡አሮንን፡— ሄደህ፡በምድረ፡በዳ፡ሙሴን፡ተገናኘው፡አለው፤ ሄዶም፡በእግዚአብሔር፡ተራራ፡ተገናኘው፥ሳመውም። ፳፰ ሙሴም፡እግዚአብሔር፡በእርሱ፡ዘንድ፡የላከውን፡ቃል፡ሁሉ፡ያዘዘውንም፡ተአምራት፡ሁሉ፡ለአሮን፡ተናገረው። ፳፱ ሙሴና፡

አሮንም ፡ ሄዱ ፡ የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ ሽማ
፴ ግሌዎች ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰቡ ። አሮንም ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ለሙሴ ፡ የነገረውን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡
ተናገረ ፥ ተአምራቱንም ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ አደ
፴፩ ረገ ። ሕዝቡም ፡ አመኑ ፤ እግዚአብሔርም ፡
የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ጐበኘ ፡ ጭንቀ
ታቸውንም ፡ እንዳየ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፥ አጐነበሱ ፡
ሰገዱም ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ሙሴና ፡ አሮን ፡ መጥተው ፡
ፈርዖንን ፡ እንዲህ ፡ አሉት ፡— የእስራኤል ፡
አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
በምድረ ፡ በዳ ፡ በዓል ፡ ያደርግልኝ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝ
፪ ቤን ፡ ልቀቅ ። ፈርዖንም ፡— ቃሉን ፡ እሰማ ፡
ዘንድ ፡ እስራኤልንስ ፡ እለቅቅ ፡ ዘንድ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ማን ፡ ነው ? እግዚአብሔርን ፡ አላው
ቅም ፥ እስራኤልንም ፡ ደግሞ ፡ አልለቅቅም ፡
፫ አለ ። እነርሱም ፡— የዕብራውያን ፡ አምላክ ፡
ተገናኘን ፤ ቸነፈር ፡ ወይም ፡ ሰይፍ ፡ እንዳይጥ
ልብን ፡ የሦስት ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ በምድረ ፡
በዳ ፡ እንድንሄድ ፥ ለአምላካችን ፡ ለእግዚአ
ብሔር ፡ እንድንሠዋ ፡ እንለምንሃለን ፡ አሉት ።
፬ የግብፅ ፡ ንጉሥም ፡— አንተ ፡ ሙሴ ፡ አንተም ፡
አሮን ፥ ሕዝቡን ፡ ለምን ፡ ሥራቸውን ፡ ታስተ
ዋላችሁ ? ወደ ፡ ተግባራችሁ ፡ ሂዱ ፡ አላቸው ።
፭ ፈርዖንም ፡— እነሆ ፡ የምድሩ ፡ ሕዝብ ፡ አሁን ፡
በዝቶአል ፥ እናንተም ፡ ሥራቸውን ፡ ታስፈቱ
፮ አቸዋላችሁ ፡ አለ ። ፈርዖንም ፡ በዚያን ፡ ቀን ፡
የሕዝቡን ፡ አስገባሪዎች ፡ ሹማምቶቹንም ፡ እን
፯ ዲህ ፡ ሲል ፡ አዘዘ ፡— እንደ ፡ ወትሮው ፡ ለጡብ ፡
ሥራ ፡ ደግሞ ፡ ገለባ ፡ ለሕዝቡ ፡ አትስጡ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ እነርሱ ፡ ሄደው ፡ ገለባ ፡ ይሰብስቡ ።
፰ ቀድሞ ፡ ያደርጉት ፡ የነበረውን ፡ የጡብ ፡ ቍጥር ፡
በእነርሱ ፡ ላይ ፡ አድርጉት ፤ ምንም ፡ ከእርሱ ፡
አታጕድሉ ፤ ሥራ ፡ ፈትተዋልና ፡ ስለዚህ ፡—
ለአምላካችን ፡ እንድንሠዋ ፡ እንሂድ ፡ እያሉ ፡
፱ ይጮኻሉ ። እርሱንም ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ በሰ
ዎች ፡ ላይ ፡ ሥራው ፡ ይክበድባቸው ፤ ከንቱ ፡
፲ ቃልም ፡ አያስቡ ። የሕዝቡም ፡ አስገባሪዎች ፡
ሹማምቶቹም ፡ ወጡ ፥ ሕዝቡንም ፡— ፈርዖን ፡
፲፩ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ገለባ ፡ አልሰጣችሁም ። እና
ንተ ፡ ሂዱ ፥ ከምታገኙበትም ፡ ሰፍራ ፡ ገለባ ፡ ሰብ
ስቡ ፡ ከሥራችሁ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ አይጐድልም ፡
፲፪ አሉአቸው ። ሕዝቡም ፡ ስለ ፡ ገለባ ፡ እብቅ ፡
ሊሰበስቡ ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ተበተኑ ።
፲፫ አስገባሪዎቹም ፡— ገለባ ፡ ትቀበሉበት ፡ እንደ ፡
ነበረ ፡ ጊዜ ፡ የቀን ፡ ሥራችሁን ፡ ጨርሱ ፡ እያሉ ፡
፲፬ አስቸኰሉአቸው ። የፈርዖንም ፡ አስገባሪዎች ፡—
ቀድሞ ፡ ታደርጉ ፡ እንደ ፡ ነበራችሁ ፡ ትናን
ትናና ፡ ዛሬ ፡ የተቈጠረውን ፡ ጡብ ፡ ስለ ፡
ምን ፡ አትጨርሱም ? እያሉ ፡ በእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ላይ ፡ የተሾሙትን ፡ አለቆቹን ፡ ገረፉ ።
፲፭ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ አለቆችም ፡ ወደ ፡ ፈር
ዖን ፡ መጡ ፡— ለምን ፡ በባሪያዎችህ ፡ እንዲህ ፡
፲፮ ታደርጋለህ ? ገለባ ፡ አይሰጡንም ፥ የጡቡንም ፡
ሥራ ፡ እንድንሠራ ፡ ያዝዙናል ፤ እነሆም ፡ ባሪያ
ዎችህን ፡ ይገርፉናል ፤ ግድፈቱ ፡ ግን ፡ በአንተ ፡
፲፯ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ጮኹ ። እርሱ ፡
ግን ፡— ሰልችታችኋል ፥ ሰልችታችኋል ፤ ስለዚ
ህም ፡— እንሂድ ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ እንሠዋ ፡
፲፰ ትላላችሁ ። አሁንም ፡ ሂዱ ፥ ሥሩ ፤ ገለባ ፡ አይ
ሰጡአችሁም ፥ የጡቡን ፡ ቍጥር ፡ ግን ፡ ታመጣ
፲፱ ላችሁ ፡ አላቸው ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ አለ
ቆች ፡— ዕለት ፡ ዕለት ፡ ከምትሠሩት ፡ ከጡቡ ፡
ቍጥር ፡ ምንም ፡ አታጕድሉ ፡ በሉአቸው ፡ ጊዜ ፡
፳ ነገሩ ፡ እንደ ፡ ከፋባቸው ፡ አዩ ። ከፈርዖንም ፡
ዘንድ ፡ ሲወጡ ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ በፊታ
፳፩ ቸው ፡ ቆመው ፡ ተገናኙአቸው ። እነርሱም ፡—
በፈርዖንና ፡ በባሪያዎቹ ፡ ፊት ፡ ሽታችንን ፡ አግ
ምታችሁታልና ፥ ይገድሉንም ፡ ዘንድ ፡ ሰይ
ፍን ፡ በእጃቸው ፡ ሰጥታችኋቸዋልና ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ይመልከታችሁ ፡ ይፍረድባችሁም ፡
አሉአቸው ።
፳፪ ሙሴም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተመለሰና ፡—
ጌታ ፡ ሆይ ፥ ስለ ፡ ምን ፡ ይህን ፡ ሕዝብ ፡ አስከ
፳፫ ፋህ ? ስለ ፡ ምንስ ፡ ላከኸኝ ? በስምህ ፡ እና
ገር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ፈርዖን ፡ ከገባሁ ፡ ወዲህ ፥
ይህን ፡ ሕዝብ ፡ አስከፍቶታልና ፤ አንተም ፡ ሕዝ
ብህን ፡ ከቶ ፡ አላዳንኸውም ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— በጸ
ናች ፡ እጅ ፡ ይለቅቃችኋልና ፥ በጸናችም ፡
እጅ ፡ ከምድሩ ፡ አስወጥቶ ፡ ይሰድዳቸዋልና ፡
አሁን ፡ በፈርዖን ፡ የማደርገውን ፡ ታያለህ ።
፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ ተናገረው ፡ አለ
፫ ውም ፡— እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ፤ ለአብር
ሃምም ፡ ለይስሐቅም ፡ ለያዕቆብም ፡ ሁሉን ፡ እን
ደሚችል ፡ አምላክ ፡ ተገለጥሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡
ስሜ ፡ እግዚአብሔር ፡ አልታወቀላቸውም ፡
፬ ነበር ። የተሰደዱበትንም ፡ ምድር ፥ የእንግድነ
ታቸውን ፡ የከነዓንን ፡ ምድር ፥ እሰጣቸው ፡
ዘንድ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ አቆ
፭ ምሁ ። ደግሞ ፡ እኔ ፡ ግብፃውያን ፡ የገዙአቸ
ውን ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ልቅሶ ፡ ሰማሁ ፤
፮ ቃል ፡ ኪዳኔንም ፡ አሰብሁ ። ስለዚህም ፡ ለእስ
ራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ በላቸው ፡— እኔ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ነኝ ፥ ከግብፃውያንም ፡ ባርነት ፡
አወጣችኋለሁ ፥ ከተገዥነታቸውም ፡ አድናች
ኋለሁ ፤ በተዘረጋ ፡ ክንድ ፡ በታላቅ ፡ ፍርድም ፡
፯ እታደጋችኋለሁ ፥ ለእኔም ፡ ሕዝብ ፡ እንድት
ሆኑ ፡ እቀበላችኋለሁ ፥ አምላክም ፡ እሆናችኋለሁ ፤
እኔም ፡ ከግብፃውያን ፡ ባርነት ፡ ያወጣኋችሁ ፡
እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡
፰ ታውቃላችሁ ። ለአብርሃምና ፡ ለይስሐቅ ፡ ለያ
ዕቆብም ፡ እሰጣት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ማልሁባት ፡
ምድር ፡ አገባችኋለሁ ፤ ርስትዋንም ፡ ርስት ፡

አድርጌ ፡ እሰጣችኋለሁ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ። ፱ ሙሴም ፡ ይህን ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተናገረ ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ ከሰውነታቸው ፡ መጨነቅ ፡ ከከባዱም ፡ ሥራ ፡ የተነሣ ፡ ቃሉን ፡ አልሰሙትም ።

፲ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፦ ፲፩ ግባ ፥ የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ ከአገሩ ፡ ይለቅቅ ፡ ዘንድ ፡ ለግብፅ ፡ ንጉሥ ፡ ለፈርዖን ፡ ንገር ። ፲፪ ሙሴም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፦ እነሆ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ አልሰሙኝም ፤ እንዴትስ ፡ ፈርዖን ፡ ይሰማኛል ? ይልቁንም ፡ እኔ ፡ ከንፈረ ፡ ቈላፍ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ። ፲፫ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ ተናገራቸው ፥ የግብፅ ፡ ንጉሥ ፡ ፈርዖንም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ከግብፅ ፡ እንዲያወጣቸው ፡ ይነግሩት ፡ ዘንድ ፡ አዘዛቸው ።

፲፬ የአባቶቻቸውም ፡ ቤት ፡ አለቆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። የእስራኤል ፡ የበኵር ፡ ልጅ ፡ የሮቤል ፡ ልጆች ፤ ሄኖኅ ፥ ፈሉስ ፥ አስሮን ፥ ከርሚ ፤ እነዚህ ፡ የሮቤል ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ። ፲፭ የስምዖንም ፡ ልጆች ፤ ይሙኤል ፥ ያሚን ፥ አሃድ ፥ ያኪን ፥ ጾሐር ፥ የከነዓናዊቱም ፡ ልጅ ፡ ሳኡል ፤ እነዚህ ፡ የስምዖን ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ። ፲፮ እነዚህም ፡ እንደ ፡ ወገኖቻቸው ፡ የሌዊ ፡ ልጆች ፡ ስሞች ፡ ጌድሶን ፥ ቀዓት ፥ ሜራሪ ፡ ናቸው ። የሌዊም ፡ የሕይወት ፡ ዘመን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ነው ። ፲፯ የጌድሶንም ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ወገኖቻቸው ፡ ሎቤኒ ፥ ሰሜኢ ፡ ናቸው ። ፲፰ የቀዓትም ፡ ልጆች ፡ እንበረም ፥ ይስዓር ፥ ኬብሮን ፥ ዑዝኤል ፡ ናቸው ፤ የቀዓትም ፡ የሕይወቱ ፡ ዘመን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ነው ። ፲፱ የሜራሪ ፡ ልጆች ፡ ሞሖሊ ፥ ሙሲ ፡ ናቸው ። እነዚህ ፡ እንደ ፡ ትውልዳቸው ፡ የሌዊ ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ። ፳ እንበረምም ፡ የአጎቱን ፡ ልጅ ፡ ዮካብድን ፡ አገባ ፥ አሮንንና ፡ ሙሴንም ፡ ወለደችለት ፤ የእንበረምም ፡ የሕይወቱ ፡ ዘመን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ነው ። ፳፩ የይስዓር ፡ ልጆች ፡ ቆሬ ፥ ናፌግ ፥ ዝክሪ ፡ ናቸው ። ፳፪ የዑዝኤል ፡ ልጆች ፡ ሚሳኤል ፥ ኤልጻፋን ፥ ሥትሪ ፡ ናቸው ። ፳፫ አሮንም ፡ የአሚናዳብን ፡ የነአሶንን ፡ እኅት ፡ ኤልሳቤጥን ፡ አገባ ፥ እርስዋም ፡ ናዳብንና ፡ አብዩድን ፡ አልዓዛርንና ፡ ኢታምርን ፡ ወለደችለት ። ፳፬ የቆሬ ፡ ልጆች ፡ አሴር ፥ ሕልቃና ፥ አብያሳፍ ፡ ናቸው ፤ እነዚህ ፡ የቆሬ ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ። ፳፭ የአሮንም ፡ ልጅ ፡ አልዓዛር ፡ ከፋትኤል ፡ ልጆች ፡ ሚስት ፡ አገባ ፥ እርስዋም ፡ ፊንሐስን ፡ ወለደችለት ። እነዚህ ፡ እንደ ፡ ወገኖቻቸው ፡ የሌዋውያን ፡ አባቶች ፡ አለቆች ፡ ናቸው ። ፳፮ እነዚህ ፡ አሮንና ፡ ሙሴ ፡ እግዚአብሔር ፦ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ በየሠራዊቶቻቸው ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ አውጡ ፡ ያላቸው ፡ ናቸው ። ፳፯ እነዚህ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ከግብፅ ፡ ያወጡ ፡ ዘንድ ፡ ከግብፅ ፡ ንጉሥ ፡ ከፈርዖን ፡ ጋር ፡ የተነጋገሩ ፡ ናቸው ፤ እነዚህ ፡ ሙሴና ፡ አሮን ፡ ናቸው ።

፳፰ እግዚአብሔርም ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ ሙሴን ፡ በተናገረው ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ ፳፱ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፦ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ፤ እኔ ፡ የምነግርህን ፡ ሁሉ ፡ ለግብፅ ፡ ንጉሥ ፡ ለፈርዖን ፡ ንገር ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ። ፴ ሙሴም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፦ እነሆ ፡ እኔ ፡ ከንፈረ ፡ ቈላፍ ፡ ነኝ ፤ እንዴትስ ፡ ፈርዖን ፡ ይሰማኛል ? አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፦ እይ ፥ እኔ ፡ ለፈርዖን ፡ አምላክ ፡ አድርጌሃለሁ ፤ ወንድምህም ፡ አሮን ፡ ነቢይ ፡ ይሆንልሃል ። ፪ ያዘዝሁህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ትነግረዋለህ ፤ ወንድምህም ፡ አሮን ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ከአገሩ ፡ ይለቅቅ ፡ ዘንድ ፡ ከፈርዖን ፡ ጋር ፡ ይናገራል ። ፫ እኔም ፡ የፈርዖንን ፡ ልብ ፡ አጸናለሁ ፥ በግብፅ ፡ ምድርም ፡ ድንቄንና ፡ ተአምራቴን ፡ አበዛለሁ ። ፬ ፈርዖንም ፡ አይሰማችሁም ፥ እጄንም ፡ በግብፅ ፡ ላይ ፡ አደርጋለሁ ፥ ሠራዊቴንም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ሕዝቤን ፡ በታላቅ ፡ ፍርድ ፡ ከግብፅ ፡ አገር ፡ አወጣለሁ ። ፭ ግብፃውያንም ፥ እጄን ፡ በግብፅ ፡ ላይ ፡ በዘረጋሁ ፡ ጊዜ ፥ የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ ከመካከላቸው ፡ ባወጣሁ ፡ ጊዜ ፥ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ። ፮ ሙሴና ፡ አሮንም ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዛቸው ፡ አደረጉ ። ፯ ፈርዖንንም ፡ በተናገሩት ፡ ጊዜ ፡ ሙሴ ፡ የሰማንያ ፡ ዓመት ፡ ሰው ፡ ነበረ ፥ አሮንም ፡ የሰማንያ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ሰው ፡ ነበረ ።

፰ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ተናገራቸው ፦ ፱ ፈርዖን ፦ ተአምራትን ፡ አሳዩኝ ፡ ሲላችሁ ፥ አሮንን ፦ በትርህን ፡ ወስደህ ፡ እባብ ፡ እንድትሆን ፡ በፈርዖን ፡ ፊት ፡ ጣላት ፡ በለው ። ፲ ሙሴና ፡ አሮንም ፡ ወደ ፡ ፈርዖን ፡ ገቡ ፥ እግዚአብሔርም ፡ እንዳዘዛቸው ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ፤ አሮንም ፡ በትሩን ፡ በፈርዖንና ፡ በባሪያዎቹ ፡ ፊት ፡ ጣለ ፥ እባብም ፡ ሆነች ። ፲፩ ፈርዖንም ፡ ጠቢባንንና ፡ መተተኞችን ፡ ጠራ ፤ የግብፅም ፡ ጠንቋዮች ፡ በአስማታቸው ፡ እንዲሁ ፡ ደግሞ ፡ አደረጉ ። ፲፪ እያንዳንዳቸውም ፡ በትራቸውን ፡ ጣሉ ፥ እባቦችም ፡ ሆኑ ፤ የአሮን ፡ በትር ፡ ግን ፡ በትራቸውን ፡ ዋጠች ። ፲፫ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፥ የፈርዖን ፡ ልብ ፡ ጸና ፥ አልሰማቸውምም ።

፲፬ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፦ የፈርዖን ፡ ልብ ፡ ደነደነ ፥ ሕዝቡንም ፡ ለመልቀቅ ፡ እንቢ ፡ አለ ። ፲፭ ማልደህ ፡ ወደ ፡ ፈርዖን ፡ ሂድ ፤ እነሆ ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ይወጣል ፥ ትገናኘውም ፡ ዘንድ ፡ አንተ ፡ በወንዝ ፡ ዳር ፡ ትቆማለህ ፤ እባብም ፡ ሆና ፡ የተለወጠችውን ፡ በትር ፡ በእጅህ ፡ ትወስዳለህ ። ፲፮ እንዲህም ፡ ትለዋለህ ፦ የዕብራውያን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፦ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንዲያገለግሉኝ ፡ ሕዝቤን ፡ ልቀቅ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡

አንተ ፡ ላከኝ ፤ እነሆም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ አልሰማህም ። ፲፯ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ በዚህ ፡ ታውቃለህ ፤ እነሆ ፡ እኔ ፡ የወንዙን ፡ ውኃ ፡ በእጄ ፡ በለችው ፡ በትር ፡ እመታለሁ ፥ ውኃውም ፡ ተለውጦ ፡ ደም ፡ ይሆናል ። ፲፰ በወንዙም ፡ ያሉት ፡ ዓሦች ፡ ይሞታሉ ፥ ወንዙም ፡ ይገማል ፤ ግብፃውያንም ፡ የወንዙን ፡ ውኃ ፡ ለመጠጣት ፡ ይጠላሉ ። ፲፱ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— አሮንን ፡— በትርህን ፡ ውሰድ ፥ ደምም ፡ እንዲሆኑ ፡ በግብፅ ፡ ውኆች ፡ በወንዞቻቸውም ፡ በመስኖቻቸውም ፡ በኩሬዎቻቸውም ፡ በውኃ ፡ ማከማቻዎቻቸውም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እጅህን ፡ ዘርጋ ፡ በለው ፤ በግብፅም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ በእንጨት ፡ ዕቃና ፡ በድንጋይ ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ደም ፡ ይሆናል ።

፳ ሙሴና ፡ አሮንም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዛቸው ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ፤ በትሩንም ፡ አንሥቶ ፥ በፈርዖንና ፡ በባሪያዎቹም ፡ ፊት ፡ የወንዙን ፡ ውኃ ፡ መታ ፤ የወንዙም ፡ ውኃ ፡ ሁሉ ፡ ተለውጦ ፡ ደም ፡ ሆነ ። ፳፩ በወንዙም ፡ የነበሩ ፡ ዓሦች ፡ ሞቱ ፤ ወንዙም ፡ ገማ ፥ ግብፃውያንም ፡ ከወንዙ ፡ ውኃ ፡ ይጠጡ ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉም ፤ ደሙም ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ነበረ ። ፳፪ የግብፅም ፡ ጠንቋዮች ፡ በአስማታቸው ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ፤ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ የፈርዖን ፡ ልብ ፡ ጸና ፥ አልሰማቸውምም ። ፳፫ ፈርዖንም ፡ ተመልሶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ገባ ፥ ይህንም ፡ ደግሞ ፡ በልቡ ፡ አላኖረውም ። ፳፬ ግብፃውያንም ፡ ሁሉ ፡ የወንዙን ፡ ውኃ ፡ ይጠጡ ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉምና ፡ በወንዙ ፡ አጠገብ ፡ ውኃ ፡ ሊጠጡ ፡ ቈፈሩ ። ፳፭ እግዚአብሔርም ፡ ወንዙን ፡ ከመታ ፡ በኋላ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ተፈጸመ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ ተናገረው ፡— ወደ ፡ ፈርዖን ፡ ግባ ፡ እንዲህም ፡ በለው ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ያገለግለኝ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝቤን ፡ ልቀቅ ። ፪ ለመልቀቅ ፡ እንቢ ፡ ብትል ፡ ግን ፡ እነሆ ፡ እኔ ፡ አገርህን ፡ ሁሉ ፡ በጓጕንቸሮች ፡ እመታለሁ ፤ ፫ ወንዙም ፡ ጓጕንቸሮችን ፡ ያፈላል ፥ ወጥተውም ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፥ ወደ ፡ መኝታ ፡ ቤትህ ፥ ወደ ፡ አልጋህም ፥ ወደ ፡ ባሪያዎችህም ፡ ቤት ፥ በሕዝብህም ፡ ላይ ፥ ወደ ፡ ምድጆችህም ፥ ወደ ፡ ቡሃቃዎችህም ፡ ይገባሉ ፤ ፬ ጓጕንቸሮችም ፡ በአንተ ፡ በሕዝብህም ፡ በባሪያዎችም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ይወጣሉ ። ፭ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— አሮንን ፡— በትርህን ፡ ይዘህ ፡ በወንዞቹና ፡ በመስኖቹ ፡ በውኃ ፡ ማከማቻዎቹም ፡ ላይ ፡ እጅህን ፡ ዘርጋ ፥ በግብፅም ፡ አገር ፡ ላይ ፡ ጓጕንቸሮችን ፡ አውጣ ፡ በለው ። ፮ አሮንም ፡ በግብፅ ፡ ውኆች ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ ዘረጋ ፤ ጓጕንቸሮቹም ፡ ወጡ ፥ የግብፅንም ፡ አገር ፡ ሸፈኑ ። ፯ ጠንቋዮችም ፡ በአስማታቸው ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ፥ በግብፅም ፡ አገር ፡ ላይ ፡ ጓጕንቸሮችን ፡ አወጡ ።

፰ ፈርዖንም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ ጠርቶ ፡— ጓጕንቸሮቹን ፡ ከእኔ ፡ ከሕዝቤም ፡ እንዲያርቅ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸልዩልኝ ፤ ለእግዚአብሔርም ፡ ይሠዋ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝቡን ፡ እለቅቃለሁ ፡ አላቸው ። ፱ ሙሴም ፡ ፈርዖንን ፡— ጓጕንቸሮቹ ፡ ከአንተ ፡ ከቤቶችህም ፡ እንዲጠፉ ፥ በወንዙም ፡ ብቻ ፡ እንዲቀሩ ፥ ለአንተ ፡ ለባሪያዎችህም ፡ ለሕዝብህም ፡ መቼ ፡ እንድጸልይ ፡ አስታውቀኝ ፡ አለው ። ፲ እርሱም ፡— ነገ ፡ አለ ። ሙሴም ፡— አምላካችንን ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚመስል ፡ እንደሌለ ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ቃልህ ፡ ይሁን ። ፲፩ ጓጕንቸሮቹም ፡ ከአንተ ፡ ከቤቶችህም ፡ ከባሪያዎችህም ፡ ከሕዝብህም ፡ ይሄዳሉ ፤ በወንዙም ፡ ብቻ ፡ ይቀራሉ ፡ አለ ። ፲፪ ሙሴና ፡ አሮንም ፡ ከፈርዖን ፡ ዘንድ ፡ ወጡ ፤ ሙሴም ፡ በፈርዖን ፡ ላይ ፡ ስላመጣቸው ፡ ጓጕንቸሮች ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኸ ። ፲፫ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴ ፡ እንዳለ ፡ አደረገ ፤ ጓጕንቸሮቹም ፡ ከቤት ፡ ከወጀድም ፡ ከሜዳም ፡ ሞቱ ። ፲፬ እንደ ፡ ክምርም ፡ አድርገው ፡ ሰበሰቡአቸው ፤ ምድርም ፡ ገማች ። ፲፭ ፈርዖንም ፡ ጸጥታ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ልቡን ፡ አደነደነ ፤ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ አልሰማቸውም ።

፲፮ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— አሮንን ፡— በትርህን ፡ ዘርጋ ፥ በግብፅም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ቅማል ፡ እንዲሆን ፡ የምድሩን ፡ ትቢያ ፡ ምታ ፡ በለው ። ፲፯ እንዲሁም ፡ አደረጉ ፤ አሮንም ፡ እጁን ፡ ዘረጋ ፥ በበትሩም ፡ የምድሩን ፡ ትቢያ ፡ መታው ፥ በሰውና ፡ በእንስሳም ፡ ላይ ፡ ቅማል ፡ ሆነ ፤ በግብፅ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ የምድር ፡ ትቢያ ፡ ሁሉ ፡ ቅማል ፡ ሆነ ። ፲፰ ጠንቋዮችም ፡ በአስማታቸው ፡ ያወጡ ፡ ዘንድ ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አልቻሉም ፤ ቅማሉም ፡ በሰውና ፡ በእንስሳ ፡ ላይ ፡ ነበረ ። ፲፱ ጠንቋዮችም ፡ ፈርዖንን ፡— ይህስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጣት ፡ ነው ፡ አሉት ፤ የፈርዖን ፡ ልብ ፡ ግን ፡ ጸና ፥ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ አልሰማቸውም ።

፳ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— ማልደህ ፡ ተነሣ ፥ በፈርዖንም ፡ ፊት ፡ ቁም ፤ እነሆ ፡ እርሱ ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ይወርዳል ፤ እንዲህም ፡ በለው ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እንዲያገለግለኝ ፡ ሕዝቤን ፡ ልቀቅ ። ፳፩ ሕዝቤንም ፡ ብትለቅቅ ፥ እነሆ ፡ በአንተ ፡ በባሪያዎችህም ፡ በሕዝብህም ፡ በቤቶችህም ፡ ላይ ፡ የዝንብ ፡ መንጎች ፡ እሰድዳለሁ ፤ የግብፃውያን ፡ ቤቶች ፡ የሚኖሩበትም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ በዝንብ ፡ መንጎች ፡ ይሞላሉ ። ፳፪ በዚያም ፡ ቀን ፡ በምድር ፡ መካከል ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፥ በዚያ ፡ የዝንብ ፡ መንጋ ፡ እንዳይሆን ፡ ሕዝቤ ፡ የሚቀመጥበትን ፡ የጌሤምን ፡ ምድር ፡ እለያለሁ ። ፳፫ በሕዝቤና ፡ በሕዝብህ ፡ መካከል ፡ እለያለሁ ፤ ይህም ፡ ተአምራት ፡ ነገ ፡ ይሆናል ። ፳፬ እግዚአብሔርም ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ፤ በፈርዖ

ንም ፡ ቤት ፡ በባሪያዎቹም ፡ ቤቶች ፡ ውስጥ ፡ ብዙ ፡
የዝንብ ፡ መንጋ ፡ መጣ ፤ በግብፅም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ ከዝንቡ ፡ መንጋ ፡ የተነሣ ፡ ምድር ፡ ጠፋች ።
፳፭ ፡ ፈርዖንም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ ጠርቶ ፦
ሂዱ ፥ በአገሩ ፡ ውስጥ ፡ ለአምላካችሁ ፡ ሠዉ ፡
፳፮ ፡ አላቸው ። ሙሴም ፦ ለእግዚአብሔር ፡ ለአም
ላካችን ፡ የግብፃውያንን ፡ ርኵሰት ፡ እንሠዋለ
ንና ፡ እንዲህ ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ አይገባም ፤
እነሆ ፡ እኛ ፡ የግብፃውያንን ፡ ርኵሰት ፡ በፊታ
፳፯ ፡ ቸው ፡ ብንሠዋ ፡ አይወግሩንምን ? እኛስ ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ ለአምላካችን ፡ እንሠዋ ፡ ዘንድ ፡
እንደሚያዝዘን ፡ የሦስት ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡
፳፰ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ እንሄዳለን ፡ አለ ። ፈርዖንም ፦
ለእግዚአብሔር ፡ ለአምላካችሁ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡
ትሠዉ ፡ ዘንድ ፡ እለቅቃችኋለሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ርቃ
፳፱ ፡ ችሁ ፡ አትሂዱ ፥ ጸልዩልኝ ፡ አለ ። ሙሴም ፦
እነሆ ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ እወጣለሁ ፥ የዝንቡም ፡
መንጎች ፡ ከፈርዖን ፡ ከባሪያዎቹም ፡ ከሕዝ
ቡም ፡ ነገ ፡ እንዲሄዱ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
እጸልይልሃለሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ይሠዋ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝቡን ፡ እንዳይለቅቅ ፡ ፈር
፴ ፡ ዖን ፡ እንደገና ፡ እያታልለን ፡ አለ ። ሙሴም ፡ ከፈ
ርዖን ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡
፴፩ ፡ ጸለየ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴ ፡ እንዳለ ፡ አደ
ረገ ፤ የዝንቡንም ፡ መንጎች ፡ ከፈርዖን ፡ ከባ
ሪያዎቹም ፡ ከሕዝቡም ፡ አስነሣ ፤ አንድ ፡ ስንኳ ፡
፴፪ ፡ አልቀረም ። ፈርዖንም ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ደግሞ ፡
ልቡን ፡ አደነደነ ፥ ሕዝቡንም ፡ አልሰቀቀም ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፦ ወደ ፡
ፈርዖን ፡ ዘንድ ፡ ግባተህ ፡ ንገረው ፦ የዕብራ
ውያን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፦ ያገለግሉኝ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝቤን ፡ ልቀቅ ።
፪ ፡ ልትለቅቃቸውም ፡ እንቢ ፡ ብትል ፡ ብትይዛቸ
፫ ፡ ውም ፥ እነሆ ፡ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ በሜዳ ፡
ውስጥ ፡ ባሉት ፡ በከብቶችህ ፥ በፈረሶችም ፡
በአህዮችም ፡ በግመሎችም ፡ በበሬዎችም ፡ በበ
ጎችም ፡ ላይ ፡ ትሆናለች ፤ ብርቱ ፡ ቸነፈርም ፡
፬ ፡ ይወርዳል ። እግዚአብሔርም ፡ በእስራኤልና ፡
በግብፅ ፡ ከብቶች ፡ መካከል ፡ ይለያል ፤ ከእስራ
ኤልም ፡ ልጆች ፡ ከብት ፡ አንዳች ፡ አይጠፋም ።
፭ ፡ እግዚአብሔርም ፦ ነገ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡
ነገር ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ያደርጋል ፡ ብሎ ፡ ጊዜን ፡
፮ ፡ ወሰነ ። እግዚአብሔርም ፡ ያንን ፡ ነገር ፡ በነ
ጋው ፡ አደረገ ፥ የግብፅም ፡ ከብት ፡ ሁሉ ፡ሞተ ፤
ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከብት ፡ ግን ፡ አንድ ፡
፯ ፡ ስንኳ ፡ አልሞተም ። ፈርዖንም ፡ ላከ ፥ እነሆም ፡
ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከብት ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡
አልሞተም ። የፈርዖን ፡ ልብ ፡ ግን ፡ ደነደነ ፥
ሕዝቡንም ፡ አልለቀቀም ።
፰ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፦ እጃ
ችሁን ፡ ሞልታችሁ ፡ ከምድጃ ፡ አመድ ፡ ውሰዱ ፥
ሙሴም ፡ በፈርዖን ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ይበ
ትነው ። እርሱም ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ትቢያ ፡ ፱ ፡
ይሆናል ፥ በግብፅም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ በሰውና ፡
በእንስሳ ፡ ላይ ፡ ሻህኝ ፡ የሚያመጣ ፡ ቍስል ፡
ይሆናል ፡ አላቸው ። ከምድጃውም ፡ አመድ ፡ ፲ ፡
ወሰዱ ፡ በፈርዖን ፡ ፊት ፡ ቆሙ ፤ ሙሴም ፡ ወደ ፡
ሰማይ ፡ በተነው ፥ በሰውና ፡ በእንስሳም ፡ ላይ ፡
ሻህኝ ፡ የሚያወጣ ፡ ቍስል ፡ ሆነ ። ጠንቋዮችም ፡ ፲፩ ፡
ቍስል ፡ ስለ ፡ ነበረባቸው ፡ በሙሴ ፡ ፊት ፡ መቆም ፡
አልቻሉም ፤ ቍስል ፡ በጠንቋዮችና ፡ በግብፃው
ያን ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነበረና ። እግዚአብሔርም ፡ የፈ ፲፪ ፡
ርዖንን ፡ ልብ ፡ አጸና ፤ እግዚአብሔር ፡ ለሙሴ ፡
እንደ ፡ ተናገረው ፡ አልሰማቸውም ።
እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፦ ማል ፲፫ ፡
ደህ ፡ ተነሣ ፥ በፈርዖንም ፡ ፊት ፡ ቆመህ ፡ በለው ፦
የዕብራውያን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፦ እንዲያገለግሉኝ ፡ ሕዝቤን ፡
ልቀቅ ። በምድር ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ እኔ ፡ ያለ ፡ ፲፬ ፡
እንደሌለ ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ በሰውነትህ ፡ በባ
ሪያዎችህም ፡ በሕዝብህም ፡ ላይ ፡ መቅሠፍቴን ፡
ሁሉ ፡ አሁን ፡ እልካለሁ ። አሁን ፡ እጄን ፡ዘር ፲፭ ፡
ግቼ ፡ አንተን ፡ ሕዝብህንም ፡ በቸነፈር ፡ በመታ
ሁህ ፡ ነበር ፥ አንተም ፡ ከምድር ፡ በጠፋህ ፡
ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ኃይሌን ፡ እገልጥብህ ፡ ዘንድ ፡ ፲፮ ፡
ስሜም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ይነገር ፡ ዘንድ ፡
ስለዚህ ፡ አስነሥቼሃለሁ ። እንዳትለቅቃቸው ፡ ፲፯ ፡
ገና ፡ በሕዝቤ ፡ ላይ ፡ ትታበያለህን ? እነሆ ፡ ነገ ፡ ፲፰ ፡
በዚህ ፡ ጊዜ ፥ ከተመሠረተች ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ያለ ፡ በግብፅ ፡ ሆኖ ፡
የማያውቅ ፥ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ በረዶ ፡ አዘንብ
ሃለሁ ። በሜዳ ፡ የተገኘ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ያልገባ ፡ ፲፱ ፡
ሰውና ፡ እንስሳ ፡ ሁሉ ፡ በረዶ ፡ ወርዶበት ፡ ይሞ
ታልና ፡ አሁን ፡ እንግዲህ ፡ ላክ ፥ ከብቶችህንም ፡
በሜዳም ፡ ያለህን ፡ ሁሉ ፡ አስቸኵል ። ከፈር ፳ ፡
ዖንም ፡ ባሪያዎች ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
የፈራ ፡ ባሪያዎቹንና ፡ ከብቶቹን ፡ ወደ ፡ ቤቶቹ ፡
አሸሸ ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ቃል ፡ ያላሰበ ፡ ፳፩ ፡
ባሪያዎቹንና ፡ ከብቶቹን ፡ በሜዳ ፡ ተወ ።
እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፦ በግብፅ ፡ አገር ፡ ፳፪ ፡
በሰው ፡ በእንስሳም ፡ በእርሻም ፡ ቡቃያ ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፥ በግብፅ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ በረዶ ፡ ይሆን ፡
ዘንድ ፡ እጅህን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ዘርጋ ፡ አለው ።
ሙሴም ፡ በትሩን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ዘረጋ ፤ እግ ፳፫ ፡
ዚአብሔርም ፡ ነጐድጓድና ፡ በረዶ ፡ ላከ ፥ እሳ
ትም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ወረደ ፤ እግዚአብሔ
ርም ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ ላይ ፡ በረዶ ፡ አዘነበ ።
በረዶም ፡ ነበረ ፥ በበረዶውም ፡ መካከል ፡ እሳት ፡ ፳፬ ፡
ይቃጠል ፡ ነበር ፥ በረዶውም ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡
ሁሉ ፡ ሕዝብ ፡ ከሆነ ፡ ጀምሮ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡
ያልሆነ ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ነበረ ። በረዶውም ፡ ፳፭ ፡
በግብፅ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ በሜዳ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡
ሰውንና ፡ እንስሳን ፡ መታ ፤ በረዶውም ፡ የእር
ሻን ፡ ቡቃያ ፡ ሁሉ ፡ መታ ፥ የአገሩንም ፡ ዛፍ ፡
ሁሉ ፡ ሰበረ ። የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተቀም ፳፮ ፡
ጠው ፡ በነበሩበት ፡ በጌሤም ፡ አገር ፡ ብቻ ፡

በረዶ ፡ አልወረደም ።

፳፯ ፈርዖንም ፡ ልኮ ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ ጠራ ፡— በዚህ ፡ ጊዜ ፡ በደልሁ ፣ እግዚአብሔር ፡ ጻድቅ ፡ ነው ፤ እኔና ፡ ሕዝቤም ፡ ኃጢአተኞች ፡ ነን ። ፳፰ የአምላክ ፡ ነጐድጓድ ፡ በረዶውም ፡ በዝቶአልና ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸልዩ ፣ እለቅቃችሁማለሁ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ በዚህ ፡ አትቀመጡም ፡ አላቸው ። ፳፱ ሙሴም ፡— ከከተማ ፡ በወጣሁ ፡ ጊዜ ፡ እጄን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እዘረጋለሁ ፣ ምድሪቱ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ ነጐድጓዱ ፡ ይቀራል ፤ በረዶውም ፡ ደግሞ ፡ አይወርድም ። ፴ ነገር ፡ ግን ፡ አንተና ፡ ባሪያዎችህ ፡ አምላክን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ገና ፡ እንደማትፈሩ ፡ አውቃለሁ ፡ አለው ። ፴፩ ገብሱ ፡ አሸቶ ፡ ተልባውም ፡ አፍርቶ ፡ ነበርና ፡ ተልባና ፡ ገብሱ ፡ ተመታ ። ፴፪ ስንዴውና ፡ አጃው ፡ ግን ፡ ጊዜው ፡ ገና ፣ ነበረና ፡ አልተመታም ። ፴፫ ሙሴም ፡ ከፈርዖን ፡ ዘንድ ፡ ከከተማ ፡ ወጣ ፤ እጁንም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘረጋ ፣ ነጐድጓዱም ፡ በረዶውም ፡ ተቋረጠ ፤ ዝናቡም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አልፈሰሰም ። ፴፬ ፈርዖንም ፡ ዝናቡ ፡ በረዶውም ፡ ነጐድጓዱም ፡ እንደ ፡ ተቋረጠ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ኃጢአትን ፡ ጨመረ ፤ እርሱና ፡ ባሪያዎቹም ፡ ልባቸውን ፡ አደነደኑ ። ፴፭ የፈርዖንም ፡ ልብ ፡ ጸና ፣ እግዚአብሔርም ፡ በሙሴ ፡ አፍ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ አልለቀቀም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፣፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ በግብፃውያን ፡ ያደረግሁትን ፡ ነገር ፡ ያደረግሁባቸውንም ፡ ተአምራቴን ፡ በልጅህ ፡ በልጅ ፡ ልጅህም ፡ ጆሮች ፡ ትነግር ፡ ዘንድ ፤ ይህችንም ፡ ተአምራቴን ፡ በመካከላቸው ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ የእርሱን ፡ የባሪያዎቹንም ፡ ልብ ፡ አደንድኜአለሁና ፡ ወደ ፡ ፈርዖን ፡ ግባ ፡ አለው ። ፫ ሙሴም ፡ አሮንም ፡ ወደ ፡ ፈርዖን ፡ ገቡ ፤ አሉትም ፡— የዕብራውያን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በፊቴ ፡ ለመዋረድ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ እንቢ ፡ ትላለህ ? ያገለግሉኝ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝቤን ፡ ልቀቅ ። ፬ ሕዝቤን ፡ ለመልቀቅ ፡ እንቢ ፡ ብትል ፡ ግን ፤ እነሆ ፡ ነገ ፡ በአገርህ ፡ አንበጣዎችን ፡ አመጣለሁ ፣ ፭ የምድሩንም ፡ ፊት ፡ ይሸፍኑታልና ፡ ምድሩን ፡ ለማየት ፡ አይቻልም ፣ ከበረዶውም ፡ አምልጦ ፡ የተረፈላችሁን ፡ ትርፍ ፡ ይበሉታል ፤ ያደገላችሁንም ፡ የእርሻውን ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ይበሉታል ፣ ፮ ቤቶችህም ፡ የባሪያዎችህም ፡ ሁሉ ፡ ቤቶች ፡ የግብፃውያንም ፡ ሁሉ ፡ ቤቶች ፡ በእነርሱ ፡ ይሞላል ፣ አባቶችህ ፡ የአባቶችህም ፡ አባቶች ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ከተቀመጡበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እስከዚህ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ያለ ፡ ያላዩት ፡ ነው ። ተመልሶም ፡ ከፈርዖን ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ። ፯ የፈርዖንም ፡ ባሪያዎች ፡— ይህ ፡ ሰው ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ዕንቅፋት ፡ ይሆንብናል ? አምላካቸውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያገለግሉት ፡ ዘንድ ፡ ሰዎችን ፡ ልቀቅ ፣ ግብፅስ ፡ እንደ ፡ ጠፋች ፡ ገና ፡ አታውቅምን ? አሉት ። ፰ ፈርዖንም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ መልሶ ፡ አስመጣቸው ፡— ሂዱ ፤ አምላካችሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አገልግሉ ፣ ነገር ፡ ግን ፡ የሚሄዱት ፡ እነማን ፡ ናቸው ? አላቸው ። ፱ ሙሴም ፡— እኛ ፡ እንሄዳለን ፤ የእግዚአብሔር ፡ በዓል ፡ ሆኖልናልና ፡ ታናናሾቻችንና ፡ ሽማግሌዎቻችን ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችንም ፡ በጎቻችንና ፡ ከብቶቻችንም ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ይሄዳሉ ፡ አለ ። ፲ ፈርዖንም ፡— እናንተን ፡ ከልጆቻችሁ ፡ ጋር ፡ ስለቅቅ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፣ ነገር ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ በፊታችሁ ፡ እንደሚሆን ፡ ተመልከቱ ። ፲፩ እንዲህም ፡ አይደለም ፣ እናንተ ፡ ወንዶቹ ፡ ሂዱ ፤ ይህን ፡ ፈልጋችኋልና ፡ እግዚአብሔርን ፡ አገልግሉ ፡ አላቸው ። ከፈርዖንም ፡ ፊት ፡ አበረሩአቸው ።

፲፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— በግብፅ ፡ አገር ፡ ላይ ፡ እንዲወጡ ፤ ከበረዶውም ፡ የተረፈውን ፡ የምድርን ፡ ቡቃያ ፡ ሁሉ ፡ እንዲበሉ ፤ ስለ ፡ አንበጣዎች ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ ላይ ፡ እጅህን ፡ ዘርጋ ፡ አለው ። ፲፫ ሙሴም ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ ላይ ፡ በትሩን ፡ ዘረጋ ፤ እግዚአብሔርም ፡ የምሥራቅን ፡ ነፋስ ፡ ያን ፡ ቀን ፡ ሁሉ ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ አመጣ ፣ ማለዳም ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ የምሥራቁ ፡ ነፋስ ፡ አንበጣዎቹን ፡ አመጣ ። ፲፬ አንበጣዎችም ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ወጡ ፤ በግብፅም ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ተቀመጡ ፣ እጅግም ፡ ብዙ ፡ ነበሩ ፣ ይህንም ፡ የሚያህል ፡ አንበጣ ፡ በፊት ፡ አልነበረም ፤ ወደ ፡ ፊትም ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ አይሆንም ። ፲፭ የምድሩንም ፡ ፊት ፡ ፈጽመው ፡ ሸፈኑት ፡ አገሪቱም ፡ ጨለመች ፣ የአገሪቱን ፡ ቡቃያ ፡ ሁሉ ፡ በረዶውም ፡ የተወውን ፡ በዛፉ ፡ የነበረውን ፡ ፍሬ ፡ ሁሉ ፡ በሉ ፣ ለምለም ፡ ነገር ፡ ዛፍም ፡ የምድር ፡ ሣርም ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ አልቀረም ። ፲፮ ፈርዖንም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ በፍጥነት ፡ ጠራ ፡— አምላካችሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እናንተንም ፡ በደልሁ ፣ ፲፯ አሁን ፡ እንግዲህ ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ ኃጢአቴን ፡ ይቅር ፡ በሉኝ ፤ ይህንም ፡ ሞት ፡ ብቻ ፡ ከእኔ ፡ ያነሣልኝ ፡ ዘንድ ፡ አምላካችሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለምኑ ፡ አላቸው ። ፲፰ ሙሴም ፡ ከፈርዖን ፡ ፊት ፡ ወጣ ፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ለመነ ። ፲፱ እግዚአብሔርም ፡ ከምዕራብ ፡ ፀውሉ ፡ ነፋሱን ፡ አስወገደ ፤ አንበጣዎችንም ፡ ወስዶ ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ ውስጥ ፡ ጣላቸው ፣ አንድ ፡ አንበጣም ፡ በግብፅ ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ አልቀረም ። ፳ እግዚአብሔር ፡ የፈርዖንን ፡ ልብ ፡ አጸና ፡ የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ አልለቀቀም ።

፳፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— እጅህን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ዘርጋ ፤ በግብፅም ፡ አገር ፡ ላይ ፡ ሰው ፡ የሚዳስሰው ፡ ጽኑ ፡ ጨለማ ፡ ይሁን ፡ አለው ።

፳፪ ሙሴም ፡ እጁን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ዘረጋ ፥ በግብፅም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ጽኑ ፡ ጨለማ ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ሆነ ፤ ፳፫ ማንም ፡ ወንድሙን ፡ አላየም ፥ ሦስት ፡ ቀንም ፡ ሙሉ ፡ ከስፍራው ፡ ማንም ፡ አልተነሣም ፤ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ በተቀመጡበት ፡ ስፍራ ፡ ብርሃን ፡ ነበራቸው ። ፳፬ ፈርዖንም ፡ ሙሴን ፡ ጠርቶ ፡— ሂዱ ፥ እግዚአብሔርን ፡ አገልግሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በጎቻችሁንና ፡ ከብቶቻችሁን ፡ ተዉ ፤ ልጆቻችሁ ፡ ደግሞ ፡ ፳፭ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይሂዱ ፡ አለው ። ሙሴም ፡— አንተ ፡ ደግሞ ፡ ለአምላካችን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የምንሠዋው ፡ መሥዋዕትንና ፡ የሚቃጠል ፡ ፳፮ መሥዋዕትን ፡ ትሰጠናለህ ። አምላካችንን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለማገልገል ፡ ከእነርሱ ፡ እንወስዳለንና ፡ ከብቶቻችን ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ይሄዳሉ ፥ አንድ ፡ ሰኰናም ፡ አይቀርም ፤ አምላካችንን ፡ የምናገለግለው ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከዚያ ፡ እስክንደ ፳፯ ርስ ፡ አናውቅም ፡ አለ ። እግዚአብሔር ፡ የፈርዖንን ፡ ልብ ፡ አጸና ፥ ሊለቅቃቸውም ፡ አልወደ ፳፰ ደም ። ፈርዖንም ፡— ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ሂድ ፤ ፊቴን ፡ በየህበት ፡ ቀን ፡ ትሞታለህና ፡ ፊቴን ፡ ፳፱ እንዳታይ ፡ ተጠንቀቅ ፡ አለው ። ሙሴም ፡— እንደ ፡ ተናገርህ ፡ ይሁን ፤ ፊትህን ፡ እንደ ፡ ገና ፡ አላይም ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— በፈርዖንና ፡ በግብፅ ፡ ላይ ፡ ገና ፡ አንዲት ፡ መቅሠፍት ፡ አመጣለሁ ፥ ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ይለቅቃችኋል ፤ ሲለቅ ፪ ቃችሁም ፡ አባርሮ ፡ ይሰድዳችኋል ። ወንዱ ፡ ከወዳጁ ፡ ሴቲቱም ፡ ከወዳጅዋ ፡ የብርና ፡ የወርቅ ፡ ዕቃ ፡ ይሹ ፡ ዘንድ ፡ በሕዝቡ ፡ ጆሮ ፡ ተናገር ፡ ፫ አለው ። እግዚአብሔርም ፡ በግብፃውያን ፡ ፊት ፡ ለሕዝቡ ፡ ሞገስን ፡ ሰጠው ። ሙሴም ፡ በፈርዖን ፡ ባሪያዎችና ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ እጅግ ፡ የከበረ ፡ ሰው ፡ ነበረ ።

፬ ሙሴም ፡ አለ ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በእኩል ፡ ሌሊት ፡ እኔ ፡ በግብፅ ፡ መካ ፭ ከል ፡ አወጣለሁ ፤ በግብፅም ፡ አገር ፡ ያለ ፡ በኵር ፡ ሁሉ ፥ በዙፋኑ ፡ ከሚቀመጠው ፡ ከፈርዖን ፡ በኵር ፡ ጀምሮ ፡ በወፍጮ ፡ አግር ፡ እስካለችው ፡ እስከ ፡ ባሪያይቱ ፡ በኵር ፡ ድረስ ፥ የከብቱም ፡ ፮ በኵር ፡ ሁሉ ፡ ይሞታል ። በግብፅም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ አስቀድሞ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ያልሆነ ፡ ኋላም ፡ ደግሞ ፡ የማይሆን ፡ ታላቅ ፡ ጩኸት ፡ ይሆናል ። ፯ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በግብፃውያንና ፡ በእስራኤል ፡ መካከል ፡ እንዲለይ ፡ እንድታውቁ ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ከሰው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ እንስሳ ፡ ድረስ ፡ ውሻ ፡ ምላሱን ፡ አያንቀሳ ፰ ቅስባቸውም ። እነዚህም ፡ ባሪያዎችህ ፡ ሁሉ ፡— አንተ ፡ ውጣ ፡ የሚከተሉህም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ይውጡ ፡ እያሉ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይወርዳሉ ፥ ለእኔም ፡ ይሰግዳሉ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እወጣለሁ ። ሙሴም ፡ በጽኑ ፡ ቁጣ ፡ ከፈርዖን ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ።

፱ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— ተአምራቴ ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ ብዙ ፡ እንዲሆን ፡ ፈርዖን ፡ አይሰማችሁም ፡ አለው ። ፲ ሙሴና ፡ አሮንም ፡ እነዚህን ፡ ተአምራቶች ፡ ሁሉ ፡ በፈርዖን ፡ ፊት ፡ አደረጉ ፤ እግዚአብሔር ፡ የፈርዖንን ፡ ልብ ፡ አጸና ፥ የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ ከአገሩ ፡ አልለቀቀም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ ሙሴንና ፡ ፪ አሮንን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— ይህ ፡ ወር ፡ የወሮች ፡ መጀመሪያ ፡ ይሁናችሁ ፤ የዓመቱም ፡ መጀመሪያ ፡ ወር ፡ ይሁናችሁ ። ፫ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ተናገሩ ፥ በሉአቸውም ፡— በዚህ ፡ ወር ፡ በአሥረኛው ፡ ቀን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ለአባቱ ፡ ቤት ፡ አንድ ፡ ጠቦት ፥ ለአንድ ፡ ቤትም ፡ አንድ ፡ ጠቦት ፡ ይውሰድ ። ፬ የቤቱ ፡ ሰዎች ፡ ቍጥርም ፡ ለጠቦቱ ፡ የማይበቃ ፡ ቢሆን ፡ እርሱና ፡ ለቤቱ ፡ የቀረበው ፡ ጎረቤቱ ፡ እንደ ፡ ነፍሶቻቸው ፡ ቍጥር ፡ አንድ ፡ ጠቦት ፡ ይውሰድ ፤ እያንዳንዱም ፡ እንደሚበላው ፡ መጠን ፡ ከጠቦቱ ፡ ይክፈሉ ። ፭ የእናንተ ፡ ጠቦት ፡ ነውር ፡ የሌለበት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ይሁን ፤ ከበጎች ፡ ወይም ፡ ከፍየሎች ፡ ውሰዱ ። ፮ በዚህም ፡ ወር ፡ እስከ ፡ አሥራ ፡ አራተኛ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ጠብቁት ፤ የእስራኤልም ፡ ማኅበር ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ ሲመሽ ፡ ይረዱት ። ፯ ከደሙም ፡ ወስደው ፡ በሚበሉበት ፡ ቤት ፡ ሁለቱን ፡ መቃንና ፡ ጉበኑን ፡ ይቅቡት ። ፰ በእሳት ፡ የተጠበሰውን ፡ ሥጋውንና ፡ ቂጣውን ፡ እንጀራ ፡ በዚያች ፡ ሌሊት ፡ ይብሉ ፤ ከመራራ ፡ ቅጠል ፡ ጋር ፡ ይበሉታል ። ፱ ጥሬውን ፡ በውኃም ፡ የበሰለውን ፡ አትብሉ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ከራሱ ፡ ከጭኑ ፡ ከሆድ ፡ ዕቃው ፡ ጋር ፡ በእሳት ፡ የተጠበሰውን ፡ ብሉት ። ፲ ከእርሱም ፡ እስከ ፡ ጥዋት ፡ አንዳች ፡ አታስቀሩ ፤ እስከ ፡ ጥዋትም ፡ የቀረውን ፡ በእሳት ፡ አቃጥሉት ። ፲፩ ወገቦቻችሁን ፡ ታጥቃችሁ ፥ ጫማችሁን ፡ በእግራችሁ ፥ በትራችሁንም ፡ በእጃችሁ ፡ አድርጋችሁ ፡ እንዲህ ፡ ብሉት ፥ ፈጥናችሁም ፡ ትበሉታላችሁ ፤ እርሱ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፋሲካ ፡ ነው ። ፲፪ እኔም ፡ በዚያች ፡ ሌሊት ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ አልፋለሁ ፥ በግብፅም ፡ አገር ፡ ከሰው ፡ እስከ ፡ እንስሳ ፡ ድረስ ፡ በኵርን ፡ ሁሉ ፡ እገድላለሁ ፤ በግብፅም ፡ አማልክት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እፈርድባቸዋለሁ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ። ፲፫ ደሙም ፡ በላችሁበት ፡ ቤቶች ፡ ምልክት ፡ ይሆንላችኋል ፤ ደሙንም ፡ በየሁ ፡ ጊዜ ፡ ከእናንተ ፡ አልፋለሁ ፤ እኔም ፡ የግብፅን ፡ አገር ፡ በመታሁ ፡ ጊዜ ፡ መቅሠፍቱ ፡ ለጥፋት ፡ አይመጣባችሁም ። ፲፬ ይህም ፡ ቀን ፡ መታሰቢያ ፡ ይሁናችሁ ፥ ለእግዚአብሔርም ፡ በዓል ፡ ታደርጉታላችሁ ፤ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ ሥርዓት ፡ ሆኖ ፡ ለዘላለም ፡ ታደርጉታላችሁ ። ፲፭ ሰባት ፡ ቀን ፡ ቂጣ ፡ እንጀራ ፡ ትበላላችሁ ፤ በመጀመሪያም ፡

ቀን ፡ እርሾውን ፡ ከቤቶቻችሁ ፡ ታወጣላችሁ ፤
ከመጀመሪያውም ፡ ቀን ፡ አንሥቶ ፡ እስከ ፡ ሰበ
ተኛው ፡ ቀን ፡ እርሾ ፡ ያለበትን ፡ እንጀራ ፡ የሚ
በላ ፡ ነፍስ ፡ ከእስራኤል ፡ ተለይቶ ፡ ይጥፋ ።
፲፮ በመጀመሪያውም ፡ ቀን ፡ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡
እንዲሁም ፡ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ የተቀደሰ ፡
ጉባኤ ፡ ይሆንላችኋል ፤ ከሚበላው ፡ በቀር ፡
በእነርሱም ፡ ምንም ፡ አትሠሩም ፥ ይህንም ፡
፲፯ ብቻ ፡ ታደርጉታላችሁ ። በዚህም ፡ ቀን ፡ ሠራ
ዊታችሁን ፡ ከግብፅ ፡ አገር ፡ አውጥቼአለሁና ፡
የቂጣውንም ፡ በዓል ፡ ጠብቁት ፤ እንግዲህ ፡
ይህን ፡ ቀን ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ ለዘላለም ፡ ሥር
፲፰ ዓት ፡ ትጠብቃላችሁ ። በመጀመሪያውም ፡
ወር ፡ በአሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡
ከወሩም ፡ እስከ ፡ ሀያ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ በመሸ ፡
፲፱ ጊዜ ፡ የቂጣ ፡ እንጀራ ፡ ትበላላችሁ ። ሰባት ፡
ቀን ፡ በቤታችሁ ፡ እርሾ ፡ አይገኝ ፤ እርሾ ፡
ያለበትንም ፡ እንጀራ ፡ የሚበላ ፡ ነፍስ ፥ ከመጻ
ተኛው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አገር ፡ ልጁ ፡ ድረስ ፥
፳ ከእስራኤል ፡ ማኅበር ፡ ተለይቶ ፡ ይጥፋ ። እርሾ ፡
ያለበትን ፡ ምንም ፡ አትብሉ ፥ በቤቶቻችሁም ፡
ሁሉ ፡ ውስጥ ፡ ቂጣ ፡ እንጀራ ፡ ብሉ ።
፳፩ ሙሴም ፡ የእስራኤልን ፡ ሽማግሌዎች ፡ ጠርቶ ፡
አላቸው ፡— ለየቤታችሁ ፡ ጠቦት ፡ ምረጡ ፥
፳፪ ወስዳችሁም ፡ ለፋሲካ ፡ እረዱት ። ከሂሶጵ ፡
ቅጠልም ፡ ጭብጥ ፡ ውሰዱ ፥ በዕቃ ፡ ውስጥ ፡
ባለውም ፡ ደም ፡ ንከሩት ፥ በዕቃውም ፡ ውስጥ ፡
ካለው ፡ ደም ፡ ሁለቱን ፡ መቃኖችና ፡ ጉበኑን ፡
እርጩ ፤ ከእናንተም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ከቤቱ ፡
፳፫ ደጅ ፡ እስኪነጋ ፡ ድረስ ፡ አይውጣ ። እግዚአ
ብሔር ፡ ግብፃውያንን ፡ ይመታ ፡ ዘንድ ፡ ያልፋ
ልና ፤ ደሙንም ፡ በጉበኑና ፡ በሁለቱ ፡ መቃ
ኖች ፡ ላይ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ በደጁ ፡
ላይ ፡ ያልፋል ፥ አጥፊውም ፡ ይመታችሁ ፡ ዘንድ ፡
፳፬ ወደ ፡ ቤታችሁ ፡ እንዲገባ ፡ አይተውም ። ለእና
ንተ ፡ ለልጆቻችሁም ፡ ለዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ አድ
፳፭ ርጋችሁ ፡ ይህችን ፡ ነገር ፡ ጠብቁ ። እንዲህም ፡
ይሆናል ፤ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ወደ
ሚሰጣችሁ ፡ አገር ፡ በገባችሁ ፡ ጊዜ ፡ ይህን ፡
፳፮ አምልኮ ፡ ጠብቁት ። እንዲህም ፡ ይሆናል ፤
ልጆቻችሁ ፡— ይህ ፡ አምልኮ ፡ ለእናንተ ፡ ምን
፳፯ ድር ፡ ነው ? በሉአችሁ ፡ ጊዜ ፥ እናንተ ፡— በግ
ብፅ ፡ አገር ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ቤቶች ፡
ላይ ፡ አልፎ ፡ ግብፃውያንን ፡ በመታ ፡ ጊዜ ፥
ቤቶቻችንን ፡ ያዳነ ፡ የእግዚአብሔር ፡ የማለፉ ፡
መሥዋዕት ፡ ይህች ፡ ናት ፡ ትሉአቸዋላችሁ ።
፳፰ ሕዝቡም ፡ ተጐንብሶ ፡ ሰገደም ። የእስራኤ
ልም ፡ ልጆች ፡ ሄዱ ፥ እንዲሁም ፡ አደረጉ ፤
እግዚአብሔር ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ እንዳዘዘ ፡
እንዲሁ ፡ አደረጉ ።
፳፱ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ እኩል ፡ ሌሊት ፡ በሆነ ፡
ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፥ በዙፋን ፡ ከተቀመጠው ፡
ከፈርዖን ፡ በኵር ፡ ጀምሮ ፡ በግዞት ፡ እስከሉት ፡
እስከ ፡ ምርኮኞቹ ፡ በኵር ፡ ድረስ ፥ የግብፃውያ
ንን ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ የተገኘውን ፡ በኵር ፡
ሁሉ ፥ የእንስሳውንም ፡ በኵሮች ፡ ሁሉ ፡ መታ ።
፴ ፈርዖንም ፡ ባሪያዎቹም ፡ ሁሉ ፡ ግብፃውያንም ፡
ሁሉ ፡ በሌሊት ፡ ተነሡ ፤ የሞተ ፡ የሌለበት ፡
ቤት ፡ አልነበረምና ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ታላቅ ፡
፴፩ ልቅሶ ፡ ሆነ ። ፈርዖንም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡
በሌሊት ፡ ጠርቶ ፡— እናንተ ፡ የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ ተነሡ ፥ ከሕዝቤ ፡ መካከል ፡ ውጡ ፤
ሂዱም ፥ እንዳላችሁም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አገ
፴፪ ልግሉ ፤ እንዳላችሁም ፡ መንጎቻችሁንና ፡ ከብ
ቶቻችሁን ፡ ውሰዱ ፥ ሂዱም ፥ እኔንም ፡ ደግሞ ፡
፴፫ ባርኩኝ ፡ አለ ። ግብፃውያንም ፡ ፈጥነው ፡
ከምድሩ ፡ ይወጡ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝቡን ፡ ያስቸኩ
ሉአቸው ፡ ነበር ፡— ሁላችን ፡ እንሞታለን ፡
፴፬ ብለዋልና ። ሕዝቡም ፡ ሊጡን ፡ ሳይቦካ ፡ ተሸ
ከሙ ፥ ቡሃቃውንም ፡ በልብሳቸው ፡ ጠቅል
፴፭ ለው ፡ በትከሻቸው ፡ ተሸከሙት ። የእስራኤ
ልም ፡ ልጆች ፡ ሙሴ ፡ እንዳዘዘ ፡ አደረጉ ፥ ከግ
ብፃውያንም ፡ የብርንና ፡ የወርቅን ፡ ዕቃ ፡ ልብ
፴፮ ስንም ፡ ለመኑ ። እግዚአብሔርም ፡ ለሕዝቡ ፡
በግብፃውያን ፡ ፊት ፡ የፈለጉትን ፡ እንዲሰጡ
አቸው ፡ ሞገስን ፡ ሰጠ ። እነርሱም ፡ ግብፃው
ያንን ፡ በዘበዙ ።
፴፯ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከራምሴ ፡ ተነሥ
ተው ፡ ወደ ፡ ሱኮት ፡ ሄዱ ፤ ከሕፃናቱም ፡ ሌላ ፡
ስድስት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ ሰው ፡ የሚያህል ፡ እግ
፴፰ ረኛ ፡ ነበረ ። ደግሞም ፡ ሌላ ፡ ብዙ ፡ ድብልቅ ፡
ሕዝብ ፡ መንጎችና ፡ ላሞችም ፡ እጅግ ፡ ብዙም ፡
፴፱ ከብቶች ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ወጡ ። ከግብፅም ፡
ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ያወጡትን ፡ ሊጥ ፡ ጋገሩ ፥
አልቦካም ፡ ነበርና ፡ ቂጣ ፡ እንጎቻ ፡ አደረ
ጉት ፤ ግብፃውያን ፡ በመውጣት ፡ ስላስቸኰሉአ
ቸው ፡ ይቈዩ ፡ ዘንድ ፡ አልተቻላቸውም ፥ ስን
፵ ቅም ፡ አላሰናዱም ፡ ነበር ። የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ የተቀመጡት ፡ ዘመን ፡
፵፩ አራት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ነው ። እንዲ
ህም ፡ ሆነ ፤ አራት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡
ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ወጣ ።
፵፪ ይህች ፡ ሌሊት ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ስላወጣቸው ፡
ለእግዚአብሔር ፡ የተጠበቀች ፡ ናት ፤ ይህች ፡
ሌሊት ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡
እስከ ፡ ልጅ ፡ ልጃቸው ፡ ድረስ ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ የተጠበቀች ፡ ናት ።
፵፫ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ አለ ፡—
ይህ ፡ የፋሲካ ፡ ሕግ ፡ ነው ፤ ከእርሱ ፡ እንግዳ ፡
፵፬ ሰው ፡ አይብላ ። በብር ፡ የተገዛ ፡ ባሪያ ፡ ቢኖር ፡
፵፭ ከተገረዘ ፡ በኋላ ፡ ከእርሱ ፡ ይብላ ። መጻተ
፵፮ ኛና ፡ ሞያተኛ ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ አይብሉ ። በአ
ንድ ፡ ቤትም ፡ ይበላ ፤ ከሥጋውም ፡ አንዳች ፡
ከቤት ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡ አታውጡ ፤ አጥንትም ፡
፵፯ አትስበሩበት ። የእስራኤልም ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡
፵፰ ያድርጉት ። እንግዳ ፡ ሰውም ፡ በመካከላችሁ ፡
ቢቀመጥ ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ ፋሲካን ፡ ሊያደ

ርግ ፡ ቢወድድ ፥ አስቀድሞ ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ ይገ
ረዝ ፥ ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ ይቅረብ ፡ ያድርግም ፤
እንደ ፡ አገር ፡ ልጅም ፡ ይሆናል ፤ ያልተገረዘ ፡
፵፱ ሁሉ ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ አይብላ ። ለአገር ፡ ልጅ ፡
በእናንተ ፡ መካከልም ፡ ለሚቀመጡ ፡ እንግዶች ፡
፶ አንድ ፡ ሥርዓት ፡ ይሆናል ። የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ፤ እግዚአብ
ሔር ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ እንዳዘዘ ፡ እንዲሁ ፡
፶፩ አደረጉ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡
የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ከሠራዊታቸው ፡ ጋር ፡
ከግብፅ ፡ ምድር ፡ አወጣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪ ተናገረው ፦ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡
ከሰውም ፡ ከእንስሳም ፡ ማሕፀንን ፡ የሚከፍት ፡
በኵር ፡ ሁሉ ፡ ለእኔ ፡ ቀድስልኝ ፤ የእኔ ፡ ነው ።
፫ ሙሴም ፡ ሕዝቡን ፡ አለ ፦ ከባርነት ፡ ቤት ፡
ከግብፅ ፡ የወጣችሁበትን ፡ ይህን ፡ ቀን ፡ አስቡ ፥
እግዚአብሔር ፡ ከዚህ ፡ ቦታ ፡ በብርቱ ፡ እጅ ፡
አውጥቶአችኋልና ፤ ስለዚህ ፡ የቦካ ፡ እንጀራ ፡
፬ አትብሉ ። እናንተ ፡ ዛሬ ፡ በአቢብ ፡ ወር ፡ ወጥ
፭ ታችኋል ። እግዚአብሔርም ፡ ለአንተ ፡ ይሰ
ጣት ፡ ዘንድ ፡ ለአባቶችህ ፡ ወደ ፡ ማለላቸው ፥
ወተትና ፡ ማር ፡ ወደምታፈስስ ፡ ምድር ፥ ወደ ፡
ከነዓናውያን ፡ ወደ ፡ ኬጢያውያንም ፡ ወደ ፡ አሞ
ራውያንም ፡ ወደ ፡ ኤዊያውያንም ፡ ወደ ፡
ኢያቡሳውያንም ፡ ምድር ፡ ባገባህ ፡ ጊዜ ፡ ይህ
ችን ፡ አምልኮ ፡ በዚህ ፡ ወር ፡ ታደርጋለህ ።
፮ ሰባት ፡ ቀን ፡ ቂጣ ፡ እንጀራ ፡ ትበላለህ ፥ በሰባ
ተኛውም ፡ ቀን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በዓል ፡ ይሆ
፯ ናል ። ሰባት ፡ ቀንም ፡ ሙሉ ፡ ቂጣ ፡ እንጀራ ፡
ትበላለህ ፥ በአንተም ፡ ዘንድ ፡ እርሾ ፡ ያለበት ፡
እንጀራ ፡ አይታይ ፥ በድንበርህም ፡ ሁሉ ፡
፰ እርሾ ፡ አይታይ ። በዚያም ፡ ቀን ፦ ከግብፅ ፡
በወጣሁ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስላደረገልኝ ፡
፱ ነው ፡ ስትል ፡ ለልጅህ ፡ ትነግረዋለህ ። እግዚ
አብሔር ፡ በብርቱ ፡ እጅ ፡ ከግብፅ ፡ አውጥቶሃ
ልና ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ በአፍህ ፡ ይሆን ፡
ዘንድ ፡ በእጅህ ፡ እንደ ፡ ምልክት ፡ በዓይኖች
ህም ፡ መካከል ፡ እንደ ፡ መታሰቢያ ፡ ይሁንልህ ።
፲ በዓመት ፡ በዓመት ፡ በወራቱ ፡ ይህችን ፡ ሥር
ዓት ፡ ጠብቃት ።
፲፩ እግዚአብሔርም ፡ ለአንተ ፡ ለአባቶችህም ፡
እንደ ፡ ማለ ፡ ወደ ፡ ከነዓናውያን ፡ ምድር ፡ ባገ
ባህ ፡ ጊዜ ፥ እርስዋንም ፡ በሰጠህ ፡ ጊዜ ፥
፲፪ ማሕፀንን ፡ የሚከፍተውን ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ ስጥ ፤ ከሚሆንልህ ፡ ከብት ፡ ሁሉ ፡ ተባት ፡
ሆኖ ፡ አስቀድሞ ፡ የተወለደው ፡ ለእግዚአብ
፲፫ ሔር ፡ ይሆናል ። የአህያውን ፡ በኵር ፡ በጠቦት ፡
ትዋጀዋለህ ፥ ባትዋጀውም ፡ አንገቱን ፡ ትሰብ
ረዋለህ ፤ የሰውንም ፡ በኵር ፡ ሁሉ ፡ ከልጆችህ ፡
፲፬ መካከል ፡ ትዋጀዋለህ ። እንዲህም ፡ ይሆናል ፤
በሚመጣው ፡ ጊዜ ፡ ልጅህ ፦ ይህ ፡ ምንድር ፡
ነው ? ብሎ ፡ በጠየቀህ ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ ትለ
ዋለህ ፦ እግዚአብሔር ፡ በብርቱ ፡ እጅ ፡ ከባር
፲፭ ነት ፡ ቤት ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ አወጣን ፤ ፈርዖ
ንም ፡ እንዳይሰድደን ፡ ልቡን ፡ ባጸና ፡ ጊዜ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ከሰው ፡ በኵር ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
እንስሳ ፡ በኵር ፡ ድረስ ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ያለ
ውን ፡ በኵር ፡ ሁሉ ፡ ገደለ ፤ ስለዚህ ፡ ወንድ ፡
ሆኖ ፡ ማሕፀንን ፡ የከፈተውን ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአ
ብሔር ፡ እሠዋለሁ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ የልጆቼን ፡
፲፮ በኵር ፡ ሁሉ ፡ እዋጃለሁ ። እግዚአብሔርም ፡
በብርቱ ፡ እጅ ፡ ከግብፅ ፡ አውጥቶናልና ፡ በእ
ጅህ ፡ እንደ ፡ ምልክት ፥ በዓይኖችህም ፡ መካ
ከል ፡ እንደ ፡ ተንጠለጠለ ፡ ነገር ፡ ይሁንልህ ።
፲፯ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ፈርዖን ፡ ሕዝቡን ፡ በለ
ቀቀ ፡ ጊዜ ፥ ምንም ፡ ቅርብ ፡ ቢሆን ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በፍልስጥኤማውያን ፡ ምድር ፡ መንገድ ፡
አልመራቸውም ፤ እግዚአብሔር ፦ ሕዝቡ ፡
ሰልፉን ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ እንዳይጸጸተው ፡ ወደ ፡
፲፰ ግብፅም ፡ እንዳይመለስ ፡ ብሎአልና ። ነገር ፡
ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ በዙሪያ ፡ መን
ገድ ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ ባለችው ፡ ምድረ ፡
በዳ ፡ መራቸው ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከግ
፲፱ ብፅ ፡ ምድር ፡ ተሰልፈው ፡ ወጡ ። ዮሴፍም ፦
እግዚአብሔር ፡ ሳይጐበኛችሁ ፡ አይቀርም ፥
አጥንቶቼንም ፡ ከዚህ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ታወ
ጣላችሁ ፡ ብሎ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ አም
ሎአቸው ፡ ነበርና ፡ ሙሴ ፡ የእርሱን ፡ አጥን
፳ ቶች ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ወሰደ ። ከሱኮትም ፡
ተጓዙ ፥ በምድረ ፡ በዳውም ፡ ዳር ፡ በኤታም ፡
፳፩ ሰፈሩ ። በቀንና ፡ በሌሊትም ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፥
መንገድ ፡ ሊያሳያቸው ፡ ቀን ፡ በደመና ፡ ዓምድ ፥
ሊያበራላቸውም ፡ ሌሊት ፡ በእሳት ፡ ዓምድ ፡
፳፪ እግዚአብሔር ፡ በፊታቸው ፡ ሄደ ። የደመና ፡
ዓምድ ፡ በቀን ፥ የእሳት ፡ ዓምድ ፡ በሌሊት ፡
ከሕዝቡ ፡ ፊት ፡ ከቶ ፡ ፈቀቅ ፡ አላለም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪ ተናገረው ፦ ተመልሰው ፡ በሚግዶልና ፡ በባ
ሕር ፡ መካከል ፥ በበአልዛፎንም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡
ባለው ፡ በፊሀሒሮት ፡ ፊት ፡ እንዲሰፍሩ ፡ ለእስ
ራኤል ፡ ልጆች ፡ ተናገር ፤ ከእርሱ ፡ አጠገብ ፡
፫ በባሕር ፡ ዳር ፡ ትሰፍራላችሁ ። ፈርዖንም ፡
ስለ ፡ እስራኤል ፡ ልጆች ፦ በምድር ፡ ይቅበዘ
በዛሉ ፥ ምድረ ፡ በዳም ፡ ዘጋቻቸው ፡ ይላል ።
፬ እኔም ፡ የፈርዖንን ፡ ልብ ፡ አጸናለሁ ፥ እርሱም ፡
ያባርራቸዋል ፤ በፈርዖንና ፡ በሠራዊቱም ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ ክብር ፡ አገኛለሁ ፤ ግብፃውያንም ፡ እኔ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ። እነ
፭ ርሱም ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ። ሕዝቡም ፡ እንደ ፡
ኰበለሉ ፡ ለግብፅ ፡ ንጉሥ ፡ ነገሩት ፤ የፈርዖ
ንና ፡ የባሪያዎቹም ፡ ልብ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ተለ
ወጠና ፦ እንዳይገዙልን ፡ እስራኤልን ፡ የለቀ
፮ ቅነው ፡ ምን ፡ አድርገናል ? አሉ ። ሰረገላው

ንም ፡ አሰናዳ ፥ ሕዝቡንም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
፯ ወሰደ ፤ ስድስት ፡ መቶ ፡ የተመረጡ ፡ ሰረገሎ
ችንም ፥ የግብፅንም ፡ ፈረሶች ፡ ሁሉ ፥ በእያ
ንዳንዱም ፡ ሰረገላ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሦስተኞችን ፡
፰ ወሰደ ። እግዚአብሔርም ፡ የግብፅን ፡ ንጉሥ ፡
የፈርዖንን ፡ ልብ ፡ አጸና ፥ እርሱም ፡ የእስራኤ
ልን ፡ ልጆች ፡ አሳደደ ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
፱ ከፍ ፡ ባለች ፡ እጅ ፡ ወጡ ። ግብፃውያንም ፥
የፈርዖን ፡ ፈረሶች ፡ ሰረገሎቹም ፡ ፈረሰኞቹም ፡
ሠራዊቱም ፡ ሁሉ ፥ አሳደዱአቸው ፤ በባሕሩ ፡
ዳር ፡ በበኣልዛፎን ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በፈ
ሀሒሮት ፡ አጠገብ ፡ ሰፍረው ፡ አገኙአቸው ።
፲ ፈርዖንም ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ዓይናቸውን ፡ አነሡ ፥ እነሆም ፡ ግብፃውያን ፡
በኋላቸው ፡ ገሥግሠው ፡ ነበር ፤ የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ እጅግ ፡ ፈሩ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡
፲፩ ጮኹ ። ሙሴንም ፦ በግብፅ ፡ መቃብር ፡ ስለ
ሌለ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንሞት ፡ ዘንድ ፡ አወ
ጣኸንን ? ከግብፅ ፡ ታወጣን ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ያደ
፲፪ ረግህብን ፡ ምንድር ፡ ነው ? በምድረ ፡ በዳ ፡ ከም
ንሞት ፡ ብንገዛላቸው ፡ ይሻላልና ፦ ተወን ፥
ለግብፃውያን ፡ እንገዛ ፡ ብለን ፡ በግብፅ ፡ ሳለን ፡
ያልንህ ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ አይደለምን ? አሉት ።
፲፫ ሙሴም ፡ ለሕዝቡ ፦ አትፍሩ ፥ ዛሬ ፡ የምታ
ዩአቸውን ፡ ግብፃውያንን ፡ ለዘላለም ፡ አታዩአ
ቸውምና ፥ ቁሙ ፥ ዛሬ ፡ ለእናንተ ፡ የሚያደርጋ
፲፬ ትን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ማዳን ፡ እዩ ። እግዚ
አብሔር ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ይዋጋል ፥ እናንተም ፡
ዝም ፡ ትላላችሁ ፡ አላቸው ።
፲፭ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፦ ለምን ፡
ትጮኽብኛለህ ? እንዲጓዙ ፡ ለእስራኤል ፡
፲፮ ልጆች ፡ ንገር ። አንተም ፡ በትርህን ፡ አንሣ ፥
እጅህንም ፡ በባሕሩ ፡ ላይ ፡ ዘርጋ ፥ ክፈለውም ፤
የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በባሕሩ ፡ ውስጥ ፡ በየ
፲፯ ብስ ፡ ያልፋሉ ። እነሆም ፡ እኔ ፡ የግብፃው
ያንን ፡ ልብ ፡ አጸናለሁ ፥ በኋላቸውም ፡ ይገባሉ ፤
በፈርዖንና ፡ በሠራዊቱም ፡ ሁሉ ፡ በሰረገሎ
ቹም ፡ በፈረሰኞቹም ፡ ላይ ፡ ክብር ፡ አገኛለሁ ።
፲፰ ግብፃውያንም ፡ በፈርዖንና ፡ በሰረገሎቹ ፡ በፈ
ረሰኞቹም ፡ ላይ ፡ ክብር ፡ ባገኘሁ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።
፲፱ በእስራኤልም ፡ ሠራዊት ፡ ፊት ፡ ይሄድ ፡ የነበ
ረው ፡ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ ፈቀቅ ፡ ብሎ ፡
በኋላቸው ፡ ሄደ ፤ የደመናውም ፡ ዓምድ ፡ ከፊ
ታቸው ፡ ፈቀቅ ፡ ብሎ ፡ በኋላቸው ፡ ቆመ ፥
፳ በግብፃውያን ፡ ሰፈርና ፡ በእስራኤል ፡ ሰፈር ፡
መካከልም ፡ ገባ ፤ በዚያም ፡ ደመናና ፡ ጨለማ ፡
ነበረ ፥ በዚህ ፡ በኩል ፡ ግን ፡ ሌሊቱን ፡ አበራ ፤
ሌሊቱንም ፡ ሁሉ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ አልተቃ
ረቡም ።
፳፩ ሙሴም ፡ በባሕሩ ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ ዘረጋ ፤ እግ
ዚአብሔርም ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ ጽኑ ፡ የምሥ
ራቅ ፡ ነፋስ ፡ አምጥቶ ፡ ባሕሩን ፡ አስወገደው ፥
ባሕሩንም ፡ አደረቀው ፥ ውኃውም ፡ ተከፈለ ።
፳፪ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በባሕሩ ፡ መካከል ፡ በየ
ብስ ፡ ገቡ ፤ ውኃውም ፡ በቀኛቸውና ፡ በግራ
፳፫ ቸው ፡ እንደ ፡ ግድግዳ ፡ ሆነላቸው ። ግብፃው
ያንም ፥ የፈርዖን ፡ ፈረሶችና ፡ ሰረገሎች ፡ ፈረ
ሰኞቹም ፡ ሁሉ ፥ እያሳደዱ ፡ በኋላቸው ፡ ወደ ፡
፳፬ ባሕር ፡ መካከል ፡ ገቡ ። ንጋትም ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡
እግዚአብሔር ፡ በእሳትና ፡ በደመና ፡ ዓምድ ፡
ሆኖ ፡ የግብፃውያንን ፡ ሠራዊት ፡ ተመለከተ ፥
፳፭ የግብፃውያንንም ፡ ሠራዊት ፡ አወከ ። የሰረገ
ሎቹንም ፡ መንኰራኵር ፡ አሰረ ፥ ወደ ፡ ጭን
ቅም ፡ አገባቸው ፤ ግብፃውያንም ፦ እግዚአ
ብሔር ፡ በግብፃውያን ፡ ላይ ፡ ይዋጋላቸዋልና ፡
ከእስራኤል ፡ ፊት ፡ እንሽሽ ፡ አሉ ።
፳፮ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፦ እጅህን ፡ በባ
ሕሩ ፡ ላይ ፡ ዘርጋ ፥ ውኃውም ፡ በግብፃውያን ፡
በሰረገሎቻቸውም ፡ በፈረሰኞቻቸውም ፡ ላይ ፡
፳፯ ይመለስ ፡ አለው ። ሙሴም ፡ እጁን ፡ በባሕሩ ፡
ላይ ፡ ዘረጋ ፥ ባሕሩም ፡ ማለዳ ፡ ወደ ፡ መፍሰሱ ፡
ተመለሰ ፤ ግብፃውያንም ፡ ከእርሱ ፡ ሸሹ ፥ እግ
ዚአብሔርም ፡ ግብፃውያንን ፡ በባሕሩ ፡ መካ
፳፰ ከል ፡ ጣላቸው ። ውኃውም ፡ ተመልሶ ፡ በኋ
ላቸው ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ የገቡትን ፡ ሰረገሎችን ፡
ፈረሰኞችንም ፡ የፈርዖንንም ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡
ከደነ ፤ ከእነርሱም ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ አልቀረም ።
፳፱ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ በባሕሩ ፡ ውስጥ ፡
በየብስ ፡ ሄዱ ፤ ውኆችም ፡ በቀኛቸውና ፡ በግ
፴ ራቸው ፡ እንደ ፡ ግድግዳ ፡ ሆኑላቸው ። እግዚ
አብሔር ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ እስራኤልን ፡ እንደዚህ ፡
ከግብፃውያን ፡ እጅ ፡ አዳነ ፤ እስራኤልም ፡ የግ
፴፩ ብፃውያንን ፡ ሬሳ ፡ በባሕር ፡ ዳር ፡ አዩ ። እስ
ራኤልም ፡ እግዚአብሔር ፡ በግብፃውያን ፡ ላይ ፡
ያደረጋትን ፡ ታላቂቱን ፡ እጅ ፡ አዩ ፥ ሕዝቡም ፡
እግዚአብሔርን ፡ ፈሩ ፥ በእግዚአብሔርም ፡
በባሪያውም ፡ በሙሴ ፡ አመኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ በዚያም ፡ ጊዜ ፡ ሙሴና ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ይህን ፡ መዝሙር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዘመሩ ፥
እንዲህም ፡ ብለው ፡ ተናገሩ ፦
በክብር ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎአልና ፡ ለእግዚ
አብሔር ፡ እዘምራለሁ ፤
ፈረሱንና ፡ ፈረሰኛውን ፡ በባሕር ፡ ጣለ ።
፪ ጕልበቴ ፡ ዝማሬዬም ፡ እግዚአብሔር ፡
ነው ፥
መድኃኒቴም ፡ ሆነልኝ ፤
ይህ ፡ አምላኬ ፡ ነው ፡ አመሰግነውማለሁ ፥
የአባቴ ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ ከፍ ፡ ከፍም ፡ አደ
ርገዋለሁ ።
፫ እግዚአብሔር ፡ ተዋጊ ፡ ነው ፥ ስሙ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ነው ፥
፬ የፈርዖንን ፡ ሰረገሎች ፡ ሠራዊቱንም ፡ በባ
ሕር ፡ ጣላቸው ፤
የተመረጡት ፡ ሦስተኞች ፡ በኤርትራ ፡
ባሕር ፡ ሰጠሙ ።

፭፤ ቀላያትም ፡ ከደኑአቸው ፤
ወደ ፡ ባሕር ፡ ጥልቀት ፡ እንደ ፡ ድንጋይ ፡ ሰጠሙ ።
፮፤ አቤቱ ÷ ቀኝህ ፡ በኃይል ፡ ከበረ ፤
አቤቱ ÷ ቀኝህ ፡ ጠላቱን ፡ አደቀቀ ።
፯፤ በክብርህም ፡ ብዛት ፡ የተነሡብህን ፡ አጠፋህ ፤
ቍጣህን ፡ ሰደድህ ÷ እንደ ፡ ገለባም ፡ በላቸው ።
፰፤ በአፍንጫህ ፡ እስትንፋስ ፡ ውኆች ፡ ተከመሩ ÷
ፈሳሾቹም ፡ እንደ ፡ ክምር ፡ ቆሙ ፤
ሞገዱም ፡ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ ረጋ ።
፱፤ ጠላትም ፡— አሳድጄ ፡ አገኛቸዋለሁ ÷
ምርኮም ፡ እካፈላለሁ ÷ ነፍሴም ፡ ትጠግባቸዋለች ፤
ሰይፌንም ፡ እመዝዛለሁ ÷ እጄም ፡ ታጠፋቸዋለች ፡ አለ ።
፲፤ ነፋስህን ፡ አነፈስህ ÷ ባሕርም ፡ ከደናቸው ፤
በኃይለኞች ፡ ውኆችም ፡ እንደ ፡ እርሳስ ፡ ሰጠሙ ።
፲፩፤ አቤቱ ÷ በአማልክት ፡ መካከል ፡ እንደ ፡ አንተ ፡ ያለ ፡ ማን ፡ ነው ?
በምስጋና ፡ የተፈራህ ÷ ድንቅንም ፡ የምታደርግ ÷
በቅድስና ፡ የከበረ ፡ እንደ ፡ አንተ ፡ ያለ ፡ ማን ፡ ነው ?
፲፪፤ ቀኝህን ፡ ዘረጋህ ÷ ምድርም ፡ ዋጠቻቸው ።
፲፫፤ በቸርነትህ ፡ የተቤዠሃቸውን ፡ ሕዝብህን ፡ መራህ ፤
በኃይልህ ፡ ወደ ፡ ቅዱስ ፡ ማደሪያህ ፡ አገባሃቸው ።
፲፬፤ አሕዛብ ፡ ሰሙ ÷ ተንቀጠቀጡም ፤
በፍልስጥኤም ፡ የሚኖሩትን ፡ ምጥ ፡ ያዛቸው ።
፲፭፤ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የኤዶም ፡ አለቆች ፡ ደነገጡ ፤
የሞዓብን ፡ ኃያላን ፡ መንቀጥቀጥ ፡ ያዛቸው ፤
በከነዓን ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ቀለጡ ።
፲፮፤ አቤቱ ÷ ሕዝብህ ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ÷
የተቤዠኸው ፡ ሕዝብ ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ÷
ፍርሃትና ፡ ድንጋጤ ፡ ወደቀባቸው ፤
በክንድህ ፡ ብርታት ፡ እንደ ፡ ድንጋይ ፡ ዝም ፡ አሉ ።
፲፯፤ አቤቱ ÷ አንተ ፡ ታስገባቸዋለህ ÷
በርስትህ ፡ ተራራም ፡ ትተክላቸዋለህ ÷
አቤቱ ÷ ለማደሪያህ ፡ ባደረግኸው ፡ ስፍራ ÷
አቤቱ ÷ እጆችህ ፡ ባዘጋጁት ፡ መቅደስ ።
፲፰፤ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለሙ ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ይነግሣል ።

፲፱፤ የፈርዖን ፡ ፈረሶች ፡ ከሰረገሎቹ ፡ ከፈረሰኞቹም ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ገቡ ÷ እግዚአብሔርም ፡ የባሕሩን ፡ ውኆች ፡ መለሰባቸው ፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ በባሕሩ ፡ መካከል ፡ በየብስ ፡ ሄዱ ። ፳፤ የአሮን ፡ እኅት ፡ ነቢይቱ ፡ ማርያም ፡ ከበሮ ፡ በእጇዋ ፡ ወሰደች ፤ ሴቶችም ፡ ሁሉ ፡ በከበሮና ፡ በዘፈን ፡ በኋላዋ ፡ ወጡ ። ፳፩፤ ማርያምም ፡ እየዘመረች ፡ መለሰችላቸው ፡—

በክብር ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎአልና ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዘምሩ ፤
ፈረሱንና ፡ ፈረሰኛውን ፡ በባሕር ፡ ጣለ ።

፳፪፤ ሙሴም ፡ እስራኤልን ፡ ከኤርትራ ፡ ባሕር ፡ አስጓዘ ÷ ወደ ፡ ሱር ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወጡ ፤ በምድረ ፡ በዳም ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ሄዱ ÷ ውኃም ፡ አላገኙም ። ፳፫፤ ወደ ፡ ማራም ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ የማራ ፡ ውኃ ፡ መራራ ፡ ነበረና ፡ ሊጠጡ ፡ አልቻሉም ፤ ስለዚህ ፡ የዚያ ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ ማራ ፡ ተብሎ ፡ ተጠራ ። ፳፬፤ ሕዝቡም ፡— ምን ፡ እንጠጣለን ? ብለው ፡ በሙሴ ፡ ላይ ፡ አንጐራጐሩ ። ፳፭፤ ሙሴም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኸ ፤ እግዚአብሔርም ፡ እንጨትን ፡ አሳየው ÷ በውኃውም ፡ ላይ ፡ ጣለው ÷ ውኃውም ፡ ጣፈጠ ። በዚያም ፡ ሥርዓትንና ፡ ፍርድን ፡ አደረገላቸው ÷ በዚያም ፡ ፈተናቸው ፤ ፳፮፤ እርሱም ፡— አንተ ፡ የአምላክህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አጥብቀህ ፡ ብትሰማ ÷ በፊቱም ፡ የሚበጀውን ፡ ብታደርግ ÷ ትእዛዙንም ፡ ብታደምጥ ÷ ሥርዓቱንም ፡ ሁሉ ፡ ብትጠብቅ ÷ በግብፃውያን ፡ ላይ ፡ ያመጣሁትን ፡ በሽታ ፡ አላደርስብህም ፤ እኔ ፡ ፈዋሽህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝና ፡ አለ ።

፳፯፤ እነርሱም ፡ ወደ ፡ ኤሊም ፡ መጡ ÷ በዚያም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ የውኃ ፡ ምንጮችና ፡ ሰባ ፡ የዘንባባ ፡ ዛፎች ፡ ነበሩበት ፤ በዚያም ፡ በውኃው ፡ አጠገብ ፡ ሰፈሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩፤ ከኤሊምም ፡ ተጓዙ ÷ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ከግብፅ ፡ አገር ፡ ከወጡ ፡ በኋላ ፡ በሁለተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአሥራ ፡ አምስተኛው ፡ ቀን ፡ በኤሊምና ፡ በሲና ፡ መካከል ፡ ወዳለችው ፡ ወደ ፡ ሲን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ መጡ ። ፪፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ በሙሴና ፡ በአሮን ፡ ላይ ፡ አንጐራጐሩ ። ፫፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡— ይህን ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ በራብ ፡ ልትገድሉ ፡ እኛን ፡ ወደዚች ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ አውጥታችኋል ፤ በሥጋው ፡ ምንቸት ፡ አጠገብ ፡ ተቀምጠን ፡ እንጀራ ፡ ስንበላ ፡ ስንጠግብ ፡ ሳለን ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ምነው ፡ በሞትን ! አሉአቸው ።

፬፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— በሕጌ ፡ ይሄዱ ፡ ወይም ፡ አይሄዱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እኔ ፡ እንድፈትናቸው ÷ እነሆ ፡ ከሰማይ ፡ እንጀራን ፡ አዘንብላችኋለሁ ፤ ሕዝቡም ፡ ወጥተው ፡ ለዕለት ፡ ለዕለት ፡ የሚበቃቸውን ፡ ይልቀሙ ። ፭፤ እንዲህም ፡ ይሆናል ፤ በስድስተኛው ፡ ቀን ፡ ያመጡትን ፡ ያዘጋጁ ÷ ዕለት ፡ ዕለትም ፡ ከሚለቅሙት ፡ ይልቅ ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ ይሁን ፡ አለው ። ፮፤ ሙሴና ፡ አሮንም ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡—

እግዚአብሔር ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ እንዳወጣ ፯ ችሁ ፡ ማታ ፡ ታውቃላችሁ ፥ የእግዚአብሔር ንም ፡ ክብር ፡ ጥዋት ፡ ታያላችሁ ፤ በእግዚአብ ሔር ፡ ላይ ፡ ያንጐራጐራችሁትን ፡ ሰምቶአልና ፤ በእኛም ፡ ላይ ፡ የምታንጐራጕሩ ፡ እኛ ፡ ምን ፰ ድር ፡ ነን ? አሉ ። ሙሴም ፡— እግዚአብሔር ፡ ያንጐራጐራችሁበትን ፡ ማንጐራጐራችሁን ፡ ሰምቶአልና ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡ ትበሉ ፡ ዘንድ ፡ ሥጋን ፥ ማልዶም ፡ ትጠግቡ ፡ ዘንድ ፡ እንጀ ራን ፡ እግዚአብሔር ፡ ይሰጣችኋል ፤ እኛም ፡ ምንድር ፡ ነን ? ማንጐራጐራችሁ ፡ በእግዚአ ብሔር ፡ ላይ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በእኛ ፡ አይደለም ፡ ፱ አለ ። ሙሴም ፡ አሮንን ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡— ማንጐራጐራችሁን ፡ ሰም ቶአልና ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቅረቡ ፡ ፲ በል ፡ አለው ። እንዲህም ፡ ሆነ ፤ አሮን ፡ ለእስ ራኤል ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ፊታቸውን ፡ አቀኑ ፤ እነሆም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ በደመናው ፡ ፲፩፡፲፪ ታየ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— የእስ ራኤልን ፡ ልጆች ፡ ማንጕርጐር ፡ ሰማሁ ፡— ወደ ፡ ማታ ፡ ሥጋን ፡ ትበላላችሁ ፥ ማለዳም ፡ እንጀ ራን ፡ ትጠግባላችሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ፡ በላቸው ።

፲፫ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በመሸ ፡ ጊዜ ፡ ድርጭቶች ፡ መጡ ፥ ሰፈሩንም ፡ ከደኑት ፤ ማለዳም ፡ በሰ ፲፬ ፈሩ ፡ ዙሪያ ፡ ጠል ፡ ወድቆ ፡ ነበር ። የወደቀ ውም ፡ ጠል ፡ ባለፈ ፡ ጊዜ ፥ እነሆ ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ደቃቅ ፡ ውርጭ ፡ ሆኖ ፡ ቅርፊት ፡ የሚመስል ፡ ደቃቅ ፡ ነገር ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ታየ ። ፲፭ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በዩት ፡ ጊዜ ፡ ያ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አላወቁምና ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡— ይህ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ተባባሉ ። ሙሴም ፡— ትበሉት ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሰጣችሁ ፡ ፲፮ እንጀራ ፡ ይህ ፡ ነው ። እግዚአብሔር ፡ ያዘ ዘው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፡— እያንዳንዱ ፡ የሚበ ላውን ፡ ያህል ፡ ይልቀም ፤ በድንኳኑ ፡ ባሉት ፡ ነፍሶች ፡ ቍጥር ፡ ለአንድ ፡ ሰው ፡ አንድ ፡ ጎሞር ፡ ፲፯ ውሰዱ ፡ አላቸው ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ፤ አንዱ ፡ አብዝቶ ፡ አንዱም ፡ ፲፰ አሳንሶ ፡ ለቀመ ። በጎሞርም ፡ በሰፈሩት ፡ ጊዜ ፡ አብዝቶ ፡ ለለቀመ ፡ አልተረፈውም ፡ ጥቂትም ፡ ለለቀመ ፡ አልጐደለበትም ፤ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ ፲፱ የሚበላውን ፡ ያህል ፡ ለቀመ ። ሙሴም ፡— ማንም ፡ ከእርሱ ፡ አንዳች ፡ ለነገ ፡ አያስቀር ፡ ፳ አላቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ ሙሴን ፡ አልሰሙትም ፤ አንዳንድ ፡ ሰዎችም ፡ ከእርሱ ፡ ለነገ ፡ አስቀሩ ፥ እርሱም ፡ ተላ ፡ ሸተተም ፤ ሙሴም ፡ ተቈጣ ቸው ።

፳፩ ሰውም ፡ ሁሉ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ የሚበላውን ፡ ያህል ፡ በጥዋት ፡ ለቀመ ፤ ፀሐይም ፡ በተኰሰ ፡ ፳፪ ጊዜ ፡ ቀለጠ ። እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በስድስተ ኛው ፡ ቀን ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ አድርገው ፡ እያን ዳንዳቸው ፡ ሁለት ፡ ጎሞር ፡ እንጀራ ፡ ለቀሙ ፤ የማኅበሩም ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ መጥተው ፡ ለሙሴ ፡ ፳፫ ነገሩት ። እርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡ የተና ገረው ፡ ይህ ፡ ነው ፡— ነገ ፡ ዕረፍት ፥ ለእግዚአ ብሔርም ፡ የተቀደሰ ፡ ሰንበት ፡ ነው ፤ የምት ጋግሩትን ፡ ጋግሩ ፥ የምትቀቅሉትንም ፡ ቀቅሉ ፥ የተረፈውን ፡ ሁሉ ፡ ለነገ ፡ እንዲጠበቅ ፡ እኑ ፳፬ ሩት ፡ አላቸው ። ሙሴም ፡ እንዳዘዘ ፡ ለነገ ፡ አኖ ሩት ፤ አልሸተተም ፥ ትልም ፡ አልሆነበትም ። ፳፭ ሙሴም ፡— የእግዚአብሔር ፡ ሰንበት ፡ ዛሬ ፡ ነውና ፡ ብሉት ፤ ዛሬ ፡ በሜዳ ፡ አታገኙትም ። ፳፮ ስድስት ፡ ቀን ፡ ልቀሙት ፤ ሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ግን ፡ ሰንበት ፡ ነው ፤ በእርሱ ፡ አይገኝም ፡ አለ ። ፳፯ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ ከሕዝቡ ፡ አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ ሊለቅሙ ፡ ወጡ ፥ ምንምን ፡ ፳፰ አላገኙም ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— ትእ ዛዞቼንና ፡ ሕጎቼን ፡ ስመጠበቅ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ፳፱ እንቢ ፡ ትላላችሁ ? እግዚአብሔር ፡ ሰንበትን ፡ እንደ ፡ ሰጣችሁ ፡ እዩ ፤ ስለዚህ ፡ በስድስተኛው ፡ ቀን ፡ የሁለት ፡ ቀን ፡ እንጀራ ፡ ሰጣችሁ ፤ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በበፍራው ፡ ይቀመጥ ፥ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ማንም ፡ ከበፍራው ፡ አይሂድ ፡ አለው ። ፴ ሕዝቡም ፡ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ዐረፈ ።

፴፩ የእስራኤልም ፡ ወገን ፡ ስሙን ፡ መና ፡ ብለው ፡ ጠሩት ፤ እርሱም ፡ እንደ ፡ ድንብላል ፡ ዘር ፡ ነጭ ፡ ነው ፤ ጣዕሙም ፡ እንደ ፡ ማር ፡ ቂጣ ፡ ፴፪ ነው ። ሙሴም ፡— እግዚአብሔር ፡ ያዘዘው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፡— ከግብፅ ፡ ምድር ፡ በወጣኋ ችሁ ፡ ጊዜ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ያበላኋችሁን ፡ እን ጀራ ፡ ያዩ ፡ ዘንድ ፡ ከእርሱ ፡ አንድ ፡ ጎሞር ፡ ሙሉ ፡ ለልጅ ፡ ልጆቻችሁ ፡ ይጠበቅ ፡ አለ ። ፴፫ ሙሴም ፡ አሮንን ፡— አንድ ፡ ማድጋ ፡ ወስደህ ፡ ጎሞር ፡ ሙሉ ፡ መና ፡ አግባበት ፥ ለልጅ ፡ ልጆ ችሁም ፡ ይጠበቅ ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፴፬ ፊት ፡ አኑረው ፡ አለው ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ እንዲሁ ፡ ይጠበቅ ፡ ዘንድ ፡ ፴፭ አሮን ፡ በምስክሩ ፡ ፊት ፡ አኖረው ። የእስራ ኤልም ፡ ልጆች ፡ ወደሚኖሩበት ፡ ምድር ፡ እስ ኪመጡ ፡ ድረስ ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ መና ፡ በሉ ፤ ወደ ፡ ከነዓን ፡ ምድር ፡ ድንበር ፡ እስኪመጡ ፡ ፴፮ ድረስ ፡ መና ፡ በሉ ። ጎሞርም ፡ የኢፍ ፡ መስ ፈሪያ ፡ አሥረኛ ፡ ክፍል ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ እንዳዘዘ ፡ ከሲን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሊጓዙ ፡ ተነሡ ፥ በራፊዲምም ፡ ሰፈሩ ፤ ሕዝ ቡም ፡ ይጠጡ ፡ ዘንድ ፡ ውኃ ፡ አልነበረም ። ፪ ሕዝቡም ፡ ሙሴን ፡ ተጣሉት ፡— የምንጠጣውን ፡ ውኃ ፡ ስጠን ፡ አሉት ። ሙሴም ፡— ስምን ፡ ትጣሉኛላችሁ ? እግዚአብሔርንስ ፡ ለምን ፡ ፫ ትፈታተናላችሁ ? አላቸው ። ሕዝቡም ፡ በዚያ ፡ በፍራ ፡ ውኃ ፡ ተጠሙ ፡— እኛንና ፡ ልጆቻች ንን ፡ ከብቶቻችንንም ፡ በጥማት ፡ ልትገድል ፡

ለምን ፡ ከግብፅ ፡ አወጣኸን ? ሲሉ ፡ በሙሴ ፡ ላይ ፡ እንጕረጐሩ ። ፬ ሙሴም ፡— ሊወግሩኝ ፡ ቀርበዋልና ፡ በዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ምን ፡ ላድርግ ? ብሎ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኸ ። ፭ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ እለፍ ፥ ከእስራኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ውሰድ ፤ ወንዙንም ፡ የመታህበትን ፡ በትር ፡ በእጅህ ፡ ይዘሃት ፡ ሂድ ። ፮ እነሆ ፡ እኔ ፡ በዚያ ፡ በኮሬብ ፡ በዓለት ፡ ላይ ፡ በፊትህ ፡ እቆማለሁ ፤ ዓለቱንም ፡ ትመታለህ ፥ ሕዝቡም ፡ ይጠጣ ፡ ዘንድ ፡ ከእርሱ ፡ ውኃ ፡ ይወጣል ፡ አለው ። ሙሴም ፡ በእስራኤል ፡ ሽማግሌዎች ፡ ፊት ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ። ፯ ስለ ፡ እስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ክርክር ፡— እግዚአብሔር ፡ በመካከላችን ፡ ነውን ፡ ወይስ ፡ አይደለም ? ሲሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ስለ ፡ ተፈታተኑት ፡ የዚያን ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ ማሳህ ፥ ደግሞም ፡ መሪባ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።

፰ አማሌቅም ፡ መጥቶ ፡ ከእስራኤል ፡ ጋር ፡ በራፊዲም ፡ ተዋጋ ። ፱ ሙሴም ፡ ኢያሱን ፡— ጕልማሶችን ፡ ምረጥልን ፥ ወጥተህም ፡ ከአማሌቅ ፡ ጋር ፡ ተዋጋ ፤ እኔ ፡ ነገ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ በትር ፡ በእጄ ፡ ይዤ ፡ በኮረብታው ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ እቆማለሁ ፡ አለው ። ፲ ኢያሱም ፡ ሙሴ ፡ እንዳለው ፡ አደረገ ፥ ከአማሌቅም ፡ ጋር ፡ ተዋጋ ፤ ሙሴና ፡ አሮንም ፡ ሆርም ፡ ወደ ፡ ኮረብታው ፡ ራስ ፡ ወጡ ። ፲፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ሙሴ ፡ እጁን ፡ በነሣ ፡ ጊዜ ፡ እስራኤል ፡ ድል ፡ ያደርግ ፡ ነበር ፤ እጁንም ፡ በወረደ ፡ ጊዜ ፡ አማሌቅ ፡ ድል ፡ ያደርግ ፡ ነበር ። ፲፪ የሙሴ ፡ እጆች ፡ ግን ፡ ከብደው ፡ ነበር ፤ ድንጋይም ፡ ወሰዱ ፥ በበታቹም ፡ አኖሩ ፥ እርሱም ፡ ተቀመጠበት ፤ አሮንና ፡ ሆርም ፡ አንዱ ፡ በዚህ ፡ አንዱ ፡ በዚያ ፡ ሆነው ፡ እጆቹን ፡ ይደግፉ ፡ ነበር ፤ ፀሐይም ፡ እስክትገባ ፡ ድረስ ፡ እጆቹ ፡ ጠነከሩ ። ፲፫ ኢያሱም ፡ አማሌቅንና ፡ ሕዝቡን ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ አሸነፈ ።

፲፬ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— የአማሌቅን ፡ ዝክር ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡ ጨርሼ ፡ እደመስሳለሁና ፡ ይህን ፡ ለመታሰቢያ ፡ በመጽሐፍ ፡ ጻፈው ፥ በኢያሱም ፡ ጆሮ ፡ ተናገር ፡ አለው ። ፲፭ ሙሴም ፡ መሠዊያ ፡ ሠራ ፥ ስሙንም ፡ ያህዌህ ፡ ንሲ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ፤ ፲፮ እርሱም ፡— እጁን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ጫነ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰልፍ ፡ በአማሌቅ ፡ ላይ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ይሁን ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ የምድያምም ፡ ካህን ፡ የሙሴ ፡ አማት ፡ ዮቶር ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሙሴና ፡ ለሕዝቡ ፡ ለእስራኤል ፡ ያደረገውን ፤ ሁሉ ፥ እግዚአብሔርም ፡ እስራኤልን ፡ ከግብፅ ፡ እንዳወጣ ፡ ሰማ ። ፪ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የሙሴ ፡ አማት ፡ ዮቶር ፡ መልሶአት ፡ የነበረውን ፡ የሙሴን ፡ ሚስት ፡ ሲፓራን ፡ ፫ ሁለቱንም ፡ ልጆችዋን ፡ ወሰደ ። ከእነርሱ ፡ የአንደኛው ፡ ስም ፡ ጌርሳም ፡ ነበረ ፤ አባቱ ፡— በሌላ ፡ አገር ፡ ስደተኛ ፡ ነበርሁ ፡ ብሎአልና ፤ ፬ የሁለተኛውም ፡ ስም ፡ አልዓዛር ፡ ነበረ ፡— የአባቴ ፡ አምላክ ፡ ረዳኝ ፥ ከፈርዖንም ፡ ሰይፍ ፡ አዳነኝ ፡ ብሎአልና ። ፭ የሙሴ ፡ አማት ፡ ዮቶርም ፡ ከልጆቹና ፡ ከሚስቱ ፡ ጋር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ተራራ ፡ አጠገብ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ወደ ፡ ሰፈረ ፡ ወደ ፡ ሙሴ ፡ መጣ ። ፮ ሙሴንም ፡— እኔ ፡ አማትህ ፡ ዮቶር ፥ ሚስትህም ፥ ከእርስዋም ፡ ጋር ፡ ሁለቱ ፡ ልጆችዋ ፡ መጥተንልሃል ፡ አለው ። ፯ ሙሴም ፡ አማቱን ፡ ሊገናኝ ፡ ወጣ ፥ ሰገደም ፥ ሳመውም ፤ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ ደኅንነታቸውን ፡ ተጠያየቁ ፥ ወደ ፡ ድንኳኑም ፡ ገቡ ። ፰ ሙሴም ፡ እግዚአብሔር ፡ በፈርዖንና ፡ በግብፃውያን ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፥ በመንገድም ፡ ያገኛቸውን ፡ ድካም ፡ ሁሉ ፥ እግዚአብሔርም ፡ እንዳዳናቸው ፡ ለአማቱ ፡ ነገረው ። ፱ ዮቶርም ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእስራኤል ፡ ስላደረገው ፡ ቸርነት ፡ ሁሉ ፥ ከግብፃውያንም ፡ እጅ ፡ ስላዳናቸው ፡ ደስ ፡ አለው ። ፲ ዮቶርም ፡— ከግብፃውያንና ፡ ከፈርዖን ፡ እጅ ፡ ያዳናችሁ ፥ ከግብፃውያንም ፡ እጅ ፡ ሕዝቡን ፡ ያዳነ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ። ፲፩ ትዕቢት ፡ ባደረጉባቸው ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአማልክት ፡ ሁሉ ፡ እንዲበልጥ ፡ አሁን ፡ አወቅሁ ፡ አለ ። ፲፪ የሙሴ ፡ አማት ፡ ዮቶርም ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕትንና ፡ ሌላ ፡ መሥዋዕትን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወሰደ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ከሙሴ ፡ አማት ፡ ጋር ፡ እንጀራ ፡ ሊበሉ ፡ አሮን ፡ የእስራኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሁሉ ፡ መጡ ።

፲፫ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በነጋው ፡ ሙሴ ፡ በሕዝቡ ፡ ሊፈርድ ፡ ተቀመጠ ፤ ሕዝቡም ፡ በሙሴ ፡ ፊት ፡ ከጥዋት ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ ቆመው ፡ ነበር ። ፲፬ የሙሴም ፡ አማት ፡ በሕዝቡ ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡— ይህ ፡ በሕዝቡ ፡ የምታደርገው ፡ ምንድር ፡ ነው ? ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ከጥዋት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ በዙሪያህ ፡ ቆመው ፡ ሳሉ ፡ አንተ ፡ ብቻህን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ተቀምጠሃል ? አለው ። ፲፭ ሙሴም ፡ አማቱን ፡— ሕዝቡ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመጠየቅ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይመጣሉ ፤ ፲፮ ነገርም ፡ ቢኖራቸው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይመጣሉ ፥ በዚህና ፡ በዚያ ፡ በሰውም ፡ መካከል ፡ እፈርዳለሁ ፥ የእግዚአብሔርንም ፡ ሥርዓትና ፡ ሕግ ፡ አስታውቃቸዋለሁ ፡ አለው ። ፲፯ የሙሴም ፡ አማት ፡ አለው ፡— አንተ ፡ የምታደርገው ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ መልካም ፡ አይደለም ። ፲፰ ይህ ፡ ነገር ፡ ይከብድብሃልና ፡ አንተ ፡ ከአንተም ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ ሕዝብ ፡ ትደክማላችሁ ፤ አንተ ፡ ብቻህን ፡ ልታደርገው ፡ አትችልም ። ፲፱ አሁንም ፡ እመክርሃለሁና ፡ ቃሌን ፡ ስማ ፥ እግዚአብሔርም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይሆናል ፤ አንተ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለሕዝቡ ፡ ሁን ፥ ነገራቸውንም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አድርስ ፤ ፳ ሥርዓቱንም ፡ ሕጉንም ፡ አስተምራቸው ፥ የሚሄዱበትን ፡ መንገድ ፡ የሚያደርጉትንም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አሳያቸው ። ፳፩ አንተም ፡

ከሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ አዋቂዎችን ÷ እግዚአብሔርን ፡
የሚፈሩትን ÷ የታመኑ ÷ የግፍንም ፡ ረብ ፡ የሚ
ጠሉትን ፡ ሰዎች ፡ ምረጥ ፤ ከእነርሱም ፡ የሺህ ፡
አለቆችን ÷ የመቶ ፡ አለቆችን ÷ የአምሳ ፡ አለ
ቆችን ÷ የአሥርም ፡ አለቆችን ፡ ሹምላቸው ።
፳፪ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ሁልጊዜ ፡ ይፍረዱ ፤ አውራ
ውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ያምጡት ÷
ታናሹንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እነርሱ ፡ ይፍረዱ ፤
እነርሱም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ሸክሙን ፡ ይሸከማሉ ÷
፳፫ ፡ ለአንተም ፡ ይቀልልልሃል ። ይህንም ፡ ብታደ
ርግ ÷ እግዚአብሔር ፡ እንዲሁ ፡ ቢያዝዝህ ÷
መቆም ፡ ይቻልሃል ÷ ደግሞም ፡ ይህ ፡ ሕዝብ ፡
ሁሉ ፡ በሰላም ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ይደርሳል ።
፳፬ ፡ ሙሴም ፡ የአማቱን ፡ ቃል ፡ሰማ ÷ ያለውንም ፡
፳፭ ፡ ሁሉ ፡ አደረገ ። ሙሴም ፡ ከእስራኤል ፡ ሁሉ ፡
አዋቂዎችን ፡ መረጠ ÷ በሕዝቡም ፡ ላይ ፡ የሺህ ፡
አለቆች ÷ የመቶም ፡ አለቆች ÷ የአምሳም ፡ አለ
ቆች ÷ የአሥርም ፡ አለቆች ፡ አድርጎ ፡ ሾማ
፳፮ ፡ ቸው ። በሕዝቡም ፡ ላይ ፡ ሁልጊዜ ፡ ፈረዱ ፤
የከበደባቸውንም ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ሙሴ ፡ አመጡ ÷
ታናሹን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ እነርሱ ፡ ፈረዱ ።
፳፯ ፡ ሙሴም ፡ እማቱን ፡ ሰደደው ፤ እርሱም ፡ ወደ ፡
አገሩ ፡ ተመለሰ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ ፡ በሦስተኛውም ፡ ወር ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ከወጡ ፡ በኋላ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡
፪ ፡ ወደ ፡ሲና ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ መጡ ። ከራፊድም ፡
ተነሥተው ፡ ወደ ፡ ሲና ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ መጡ ÷
በምድረ ፡ በዳም ፡ ሰፈሩ ፤ በዚያም ፡ እስራ
፫ ፡ ኤል ፡ በተራራው ፡ ፊት ፡ ሰፈረ ። ሙሴም ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ፤ እግዚአ
ብሔርም ፡ በተራራው ፡ ጠርቶ ፡ አለው ፦ ለያ
ዕቆብ ፡ ቤት ፡ እንዲህ ፡ በል ÷ ለእስራኤልም ፡
፬ ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ንገር ፦ በግብፃውያን ፡ ያደ
ረግሁትን ÷ በንስርም ፡ ክንፍ ፡ እንደ ፡ ተሸከም
ኋችሁ ÷ ወደ ፡ እኔም ፡ እንዳመጣኋችሁ ፡ አይ
፭ ፡ ታችኋል ። አሁንም ፡ ቃሌን ፡ በእውነት ፡ ብት
ሰሙ ፡ ኪዳኔንም ፡ ብትጠብቁ ÷ ምድር ፡ ሁሉ ፡
የእኔ ፡ ናትና ፡ ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ የተመረጠ ፡
፮ ፡ ርስት ፡ ትሆኑልኛላችሁ ፤ እናንተም ፡ የካህናት ፡
መንግሥት ፡ የተቀደሰም ፡ ሕዝብ ፡ ትሆኑልኛላ
ችሁ ። ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የምትነግራቸው ፡
ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ።
፯ ፡ ሙሴም ፡ መጣ ÷ የሕዝቡንም ፡ሽማግሌዎች ፡
ጠርቶ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያዘዘውን ፡ ይህን ፡ ቃል ፡
፰ ፡ ሁሉ ፡ በፊታቸው ፡ ተናገረ ። ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡
አንድ ፡ አፍ ፡ ሆነው ፦ እግዚአብሔር ፡ ያለ
ውን ፡ ሁሉ ፡ እናደርጋለን ፡ ብለው ፡ መለሱ ፤
ሙሴም ፡ የሕዝቡን ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
፱ ፡ ሔር ፡ አደረሰ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፦
ከአንተ ፡ ጋር ፡ ስነጋገር ፡ ሕዝቡ ፡ እንዲሰሙ ÷
ደግሞም ፡ ለዘላለም ፡ እንዲያምኑብህ ÷ እነሆ ፡
በከበድ ፡ ደመና ፡ እመጣልሃለሁ ፡ አለው ።
ሙሴም ፡ የሕዝቡን ፡ ቃል ፡ ለእግዚአብሔር ፡
፲ ፡ ነገረ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፦
ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ ሂድ ÷ ዛሬና ፡ ነገም ፡ ቀድሳቸው ÷
፲፩ ፡ ልብሳቸውንም ፡ ይጠቡ ፤ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡
ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ሲያዩ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሲና ፡
ተራራ ፡ ላይ ፡ ይወርዳልና ፡ ለሦስተኛው ፡ ቀን ፡
፲፪ ፡ ይዘጋጁ ። ወሰንም ፡ ለሕዝቡ ፡ በዙሪያው ፡
አድርግላቸው ፦ ወደ ፡ ተራራው ፡ እንዳት
ወጡ ፡ ጫፉንም ፡ እንዳትነኩ ፡ ተጠንቀቁ ፤ ተራ
፲፫ ፡ ራውንም ፡ የነካ ፡ ፈጽሞ ፡ ይሞታል ፤ የማ
ንም ፡ እጅ ፡ አይንካ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የሚነካው ፡
ሁሉ ፡ ይወገራል ÷ ወይም ፡ በፍላጻ ፡ ይወጋል ፤
እንስሳ ፡ ወይም ፡ ሰው ፡ ቢሆን ፡ አይድንም ፡
በላቸው ። ሳያቋርጥ ፡ የመለከት ፡ ድምፅ ፡
ሲነፋ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ተራራው ፡ ይውጡ ።
፲፬ ፡ ሙሴም ፡ ከተራራው ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ ወረደ ÷
ሕዝቡንም ፡ ቀደሰ ፤ ልብሳቸውንም ፡ አጠቡ ።
፲፭ ፡ ሕዝቡንም ፦ ለሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ተዘጋጁ ÷
ወደ ፡ ሴቶቻችሁ ፡ አትቅረቡ ፡ አለ ።
፲፮ ፡ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ በማ
ለዳ ፡ ጊዜ ፡ ነጐድጓድና ፡ መብረቅ ፡ ከባድም ፡
ደመና ፡ እጅግም ፡ የበረታ ፡ የቀንደ ፡ መለከት ፡
ድምፅ ፡ በተራራው ፡ ላይ ፡ ሆነ ፤ በሰፈሩም ፡
፲፯ ፡ የነበሩት ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ተንቀጠቀጡ ። ሙሴም ፡
ሕዝቡን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ ለማገናኘት ፡
ከሰፈር ፡ አወጣቸው ፤ ከተራራውም ፡ እግርጌ ፡
፲፰ ፡ ቆሙ ። እግዚአብሔርም ፡ በእሳት ፡ ስለ ፡ ወረ
ደበት ፡ የሲና ፡ ተራራ ፡ ሁሉ ፡ ይጤስ ፡ ነበር ፤
ከእርሱም ፡ እንደ ፡ እቶን ፡ ጢስ ፡ ያለ ፡ ጢስ ፡
ይወጣ ፡ ነበር ÷ ተራራውም ፡ ሁሉ ፡ እጅግ ፡
፲፱ ፡ ይናወጥ ፡ ነበር ። የቀንደ ፡ መለከቱም ፡ ድምፅ ፡
እጅግ ፡ በበረታና ፡ በጸና ፡ ጊዜ ፡ ሙሴ ፡ ተና
ገረ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በድምፅ ፡ መለሰለት ።
፳ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በሲና ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ወደ ፡
ተራራው ፡ ራስ ፡ ወረደ ፤ እግዚአብሔርም ፡
ሙሴን ፡ ወደ ፡ ተራራው ፡ ራስ ፡ ጠራው ፤
፳፩ ፡ ሙሴም ፡ ወጣ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፦
ውረድ ÷ እግዚአብሔርን ፡ ለማየት ፡ ዳርቻውን ፡
እንዳያልፉ ፡ ከእነርሱም ፡ ብዙ ፡ እንዳይጠፉ ፡
፳፪ ፡ ለሕዝቡ ፡ አስጠንቅቃቸው ፤ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔርም ፡ የሚቀርቡት ፡ ካህናት ፡ ደግሞ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንዳያጠፋቸው ፡ ራሳቸውን ፡ ይቀ
፳፫ ፡ ድሱ ፡ አለው ። ሙሴም ፡ እግዚአብሔርን ፦
አንተ ፦ በተራራው ፡ ዙሪያ ፡ ወሰን ፡ አድርግ ፡
ቀድሰውም ፡ ብለህ ፡ አስጠንቅቀኸናልና ፡ ሕዝቡ ፡
ወደ ፡ ተራራ ፡ ይወጡ ፡ ዘንድ ፡ አይችሉም ፡
፳፬ ፡ አለው ። እግዚአብሔርም ፦ ሂድ ÷ ውረድ ፤
አንተ ፡ አሮንም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ትወጣላችሁ ፤
ካህናቱና ፡ ሕዝቡ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳ
ያጠፋቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይወጡ ፡
፳፭ ፡ ዘንድ ፡ አይተላለፉ ፡ አለው ። ሙሴም ፡ ወደ ፡
ሕዝቡ ፡ ወረደ ÷ ይህንንም ፡ ነገራቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩፤ እግዚአብሔርም ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ፡— ፪፤ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ከባርነት ፡ ቤት ፡ ያወጣሁህ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ እኔ ፡ ነኝ ።

፫፤ ከእኔ ፡ በቀር ፡ ሌሎች ፡ አማልክት ፡ አይሁኑልህ ።

፬፤ በላይ ፡ በሰማይ ፡ ካለው ፥ በታችም ፡ በምድር ፡ ካለው ፥ ከምድርም ፡ በታች ፡ በውኃ ፡ ካለው ፡ ነገር ፡ የማናቸውንም ፡ ምሳሌ ፥ የተቀረጸውንም ፡ ምስል ፡ ለአንተ ፡ አታድርግ ። ፭፤ አትስገድላቸው ፥ አታምልካቸውምም ፤ በሚጠሉኝ ፡ እስከ ፡ ሦስተኛና ፡ እስከ ፡ አራተኛ ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ የአባቶችን ፡ ኃጢአት ፡ በልጆች ፡ ላይ ፡ የማመጣ ፤ ፮፤ ለሚወድዱኝ ፥ ትእዛዜንም ፡ ለሚጠብቁ ፡ እስከ ፡ ሺህ ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ ምሕረትን ፡ የማደርግ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ ቀናተኛ ፡ አምላክ ፡ ነኝና ።

፯፤ የእግዚአብሔርን ፡ የአምላክህን ፡ ስም ፡ በከንቱ ፡ አትጥራ ፤ እግዚአብሔር ፡ ስሙን ፡ በከንቱ ፡ የሚጠራውን ፡ ከበደል ፡ አያነጻውምና ።

፰፤ የሰንበትን ፡ ቀን ፡ ትቀድሰው ፡ ዘንድ ፡ አስብ ። ፱፤ ስድስት ፡ ቀን ፡ ሥራ ፡ ተግባርህንም ፡ ሁሉ ፡ አድርግ ፤ ፲፤ ሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ግን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለአምላክህ ፡ ሰንበት ፡ ነው ፤ አንተ ፥ ወንድ ፡ ልጅህም ፥ ሴት ፡ ልጅህም ፥ ሎሌህም ፥ ገረድህም ፥ ከብትህም ፥ በደጆችህም ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ እንግዳ ፡ በእርሱ ፡ ምንም ፡ ሥራ ፡ አትሥራ ፤ ፲፩፤ እግዚአብሔር ፡ በስድስት ፡ ቀን ፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፥ ባሕርንም ፥ ያለባቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ፈጥሮ ፡ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ዐርፎአልና ፤ ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሰንበትን ፡ ቀን ፡ ባርኮታል ፡ ቀድሶታልም ።

፲፪፤ አባትህንና ፡ እናትህን ፡ አክብር ፤ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ በሚሰጥህ ፡ ምድር ፡ ዕድሜህ ፡ እንዲረዝም ።

፲፫፤ አትግደል ።

፲፬፤ አታመንዝር ።

፲፭፤ አትስረቅ ።

፲፮፤ በባልንጀራህ ፡ ላይ ፡ በሐሰት ፡ አትመስክር ።

፲፯፤ የባልንጀራህን ፡ ቤት ፡ አትመኝ ፤ የባልንጀራህን ፡ ሚስት ፡ ሎሌውንም ፡ ገረዱንም ፡ በሬውንም ፡ አህያውንም ፡ ከባልንጀራህ ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉ ፡ ማናቸውንም ፡ አትመኝ ።

፲፰፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ነጐድጓዱንና ፡ መብረቁን ፥ የቀንደ ፡ መለከቱን ፡ ድምፅ ፥ ተራራውንም ፡ ሲጤስ ፡ አዩ ፤ ሕዝቡም ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ተርበደበዱ ፥ ርቀውም ፡ ቆሙ ። ፲፱፤ ሙሴንም ፡— አንተ ፡ ተናገረን ፡ እኛም ፡ እንሰማለን ፤ እንዳንሞት ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ አይናገረን ፡ አሉት ። ፳፤ ሙሴም ፡ ለሕዝቡ ፡— እግዚአብሔር ፡ ሊፈትናችሁ ፥ ኃጢአትንም ፡ እንዳትሠሩ ፡ እርሱን ፡ መፍራት ፡ በልባችሁ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ መጥቶአልና ፡ አትፍሩ ፡ አለ ። ፳፩፤ ሕዝቡም ፡ ርቀው ፡ ቆሙ ፥ ሙሴም ፡ እግዚአብሔር ፡ ወዳለበት ፡ ወደ ፡ ጨለማው ፡ ቀረበ ።

፳፪፤ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ በል ፡— እኔ ፡ ከሰማይ ፡ እንደ ፡ ተናገርኋችሁ ፡ እናንተ ፡ አይታችኋል ። ፳፫፤ በእጠገቤ ፡ ምንም ፡ አታድርጉ ፤ የብር ፡ አማልክት ፡ የወርቅም ፡ አማልክት ፡ ለእናንተ ፡ አታድርጉ ። ፳፬፤ የጭቃ ፡ መሠዊያ ፡ ሥራልኝ ፥ የሚቃጠለውንና ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋዕትህን ፡ በጎችህንም ፡ በሬዎችህንም ፡ ሠዋበት ፤ ስሜን ፡ በማሳስብበት ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ መጥቼ ፡ እባርክሃለሁ ። ፳፭፤ የድንጋይም ፡ መሠዊያ ፡ ብታደርግልኝ ፡ ብረት ፡ በነካው ፡ ድንጋይ ፡ አትሥራው ፤ በመግረዝ ፡ ብትነካው ፡ ታረክሰዋለህና ። ፳፮፤ ኃፍረተ ፡ ሥጋህ ፡ በእርሱ ፡ እንዳይገለጥ ፡ ወደ ፡ መሠዊያዬ ፡ በደረጃ ፡ አትውጣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩፤ በፊታቸው ፡ የምታደርገው ፡ ሥርዓት ፡ ይህ ፡ ነው ። ፪፤ ዕብራዊ ፡ ባሪያ ፡ የገዛህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ያገልግልህ ፥ በሰባተኛውም ፡ በከንቱ ፡ አርነት ፡ ይውጣ ። ፫፤ ብቻውን ፡ መጥቶ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ብቻውን ፡ ይውጣ ፤ ከሚስቱ ፡ ጋር ፡ መጥቶ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሚስቱ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ትውጣ ። ፬፤ ጌታው ፡ ሚስት ፡ አጋብቶት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ወንዶች ፡ ወይም ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ብትወልድለት ፥ ሚስቱና ፡ ልጆችዋ ፡ ለጌታው ፡ ይሁኑ ፥ እርሱም ፡ ብቻውን ፡ ይውጣ ። ፭፤ ባሪያውም ፡— ጌታዬን ፡ ሚስቴን ፡ ልጆቼንም ፡ እወድዳለሁ ፥ አርነት ፡ አልወጣም ፡ ብሎ ፡ ቢናገር ፥ ፮፤ ጌታው ፡ ወደ ፡ ፈራጆች ፡ ይውሰደው ፥ ወደ ፡ ደጁም ፡ ወደ ፡ መቃኑ ፡ አቅርቦ ፡ ጆሮውን ፡ በወስፌ ፡ ይብሳው ፤ ለዘላለምም ፡ ባሪያው ፡ ይሁን ።

፯፤ ሰውም ፡ ሴት ፡ ልጁን ፡ ለባርነት ፡ ቢሸጥ ፡ ባሪያዎች ፡ እንደሚወጡ ፡ እርስዋ ፡ አትውጣ ። ፰፤ ጌታዋን ፡ ደስ ፡ ባታሰኘው ፡ በዋጆ ፡ ይለደዳት ፤ ስለ ፡ ናቃት ፡ ለሌላ ፡ ወገን ፡ ሰዎች ፡ ይሸጣት ፡ ዘንድ ፡ አይገባውም ። ፱፤ ለልጁም ፡ ቢድራት ፥ ለሴት ፡ ልጆች ፡ የሚገባውን ፡ ያድርግላት ። ፲፤ ከእርስዋ ፡ ሌላም ፡ ቢያጋባው ፥ መኖዋን ፡ ልብሰዋንም ፡ ለምንጣፍዋም ፡ ተገቢውን ፡ አያጕድልባት ። ፲፩፤ ይህንም ፡ ሦስት ፡ ነገር ፡ ባያደርግላት ፡ ያለ ፡ ገንዘብ ፡ በከንቱ ፡ ትውጣ ።

፲፪፤ ሰው ፡ ሰውን ፡ ቢመታ ፡ ቢሞትም ፥ እርሱ ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደል ። ፲፫፤ ባይሸምቅበትም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ድንገት ፡ በእጁ ፡ ቢጥለው ፥ የሚሸሽበት ፡ ስፍራ ፡ እኔ ፡ አደርግልሃለሁ ። ፲፬፤ ሰው ፡ ግን ፡ ቢደፍር ፥ ባልንጀራውን ፡ በተንኰል ፡ ቢገድለው ፥ እንዲሞት ፡ ከመሠዊያዬ ፡ አውጥተህ ፡ ውሰደው ።

፲፭፤ አባቱን ፡ ወይም ፡ እናቱን ፡ የሚመታ ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደል ።

፲፮፤ ሰውን ፡ ሰርቆ ፡ ቢሸጥ ፥ ወይም ፡ በእጁ ፡ ቢገኝ ፥

እርሱ ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደል ።
፲፯ አባቱን፡ወይም፡እናቱን፡የሚሰድብ፡ፈጽሞ፡
ይገደል ።
፲፰ ሁለት ፡ ሰዎችም ፡ ቢጣሉ ÷ አንዱም ፡ ሌላ
ውን ፡ በድንጋይ ፡ ወይም ፡ በጡጫ ፡ ቢመታ ÷
ያም ፡ ባይሞት ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ታምሞ ፡ በአልጋው ፡
፲፱ ላይ ፡ ቢተኛ ÷ ተነሥቶም ፡ በምርኩዝ ፡ ወደ ፡
ሜዳ ፡ ቢወጣ ÷ የመታው ፡ ንጹሕ ፡ ነው ፤ ነገር ፡
ግን ፡ ተግባሩን ፡ ስላስፈታው ፡ ገንዘብ ፡ ይከፍ
ለው ፡ ዘንድ ÷ ያስፈውስውም ፡ ዘንድ ፡ ግዴታ ፡
አለበት ።
፳ ሰውም ፡ ወንድ ፡ ባሪያውን ፡ ወይም ፡ ሴት ፡
ባሪያውን ፡ በበትር ፡ ቢመታ ÷ ቢሞትበትም ÷
፳፩ ፈጽሞ ፡ ይቀጣ ። የተመታው ፡ ግን ፡ አንድ ፡
ወይም ፡ ሁለት ፡ ቀን ፡ ቢቈይ ፡ ገንዘቡ ፡ ነውና ፡
አይቀጣ ።
፳፪ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ቢጣሉ ÷ ያረገዘችንም ፡ ሴት ፡
ልጁን ፡ እስክትጨነግፍ ፡ ቢገፉአት ፡ በትጕዳ ፡
ግን ÷ የሴቲቱ ፡ ባል ፡ የጫነበትን ፡ ያህል ፡
ካሳ ፡ ይስጥ ፤ ፈራጆቹም ፡ እንደ ፡ ፈረዱበት ፡
፳፫ ይክፈል ። ጕዳት ፡ ግን ፡ ቢያገኛት ፡ ሕይወት ፡
፳፬ በሕይወት ÷ ዓይን ፡ በዓይን ÷ ጥርስ ፡ በጥርስ ÷
፳፭ እጅ ፡ በእጅ ÷ እግር ፡ በእግር ÷ መቃጠል ፡
በመቃጠል ÷ ቍስል ፡ በቍስል ÷ ግርፋት ፡ በግ
ርፋት ፡ ይክፈል ።
፳፮ ሰውም ፡ የባሪያውን ፡ ወይም ፡ የባሪያይቱን ፡
ዓይን ፡ ቢመታ ፡ ቢያጠፋውም ÷ ስለ ፡ ዓይኑ ፡
፳፯ አርነት ፡ ያውጣው ። የባሪያውን ፡ ወይም ፡
የባሪያይቱን ፡ ጥርስ ፡ ቢሰብር ÷ ስለ ፡ ጥርሱ ፡
አርነት ፡ ያውጣው ።
፳፰ በሬም ፡ ወንድን ፡ ወይም ፡ ሴትን ፡ እስኪሞቱ ፡
ድረስ ፡ ቢወጋ ÷ በሬው ፡ ይወገር ÷ ሥጋውም ፡
አይበላ ፤ የበሬው ፡ ባለቤት ፡ ግን ፡ ንጹሕ ፡ ነው ።
፳፱ በሬው ፡ ግን ፡ አስቀድሞ ፡ ተዋጊ ፡ ቢሆን ÷
ሰዎችም ፡ ስባለቤቱ ፡ ቢመሰክሩለት ፡ ባይጠብ
ቀውም ÷ ወንድንም ፡ ወይም ፡ ሴትን ፡ ቢገ
ድል ÷ በሬው ፡ ይወገር ÷ ባለቤቱ ፡ ደግሞ ፡ ይገ
፴ ደል ። ከእርሱ ፡ ግን ፡ ካሳ ፡ ቢፈልጉ ÷ የሕይ
ወቱን ፡ ዋጋ ፡ የጫኑበትን ፡ ያህል ፡ ይስጥ ።
፴፩ ደግሞ ፡ ወንድን ፡ ልጅ ፡ ቢወጋ ፡ ሴትንም ፡
ልጅ ፡ ቢወጋ ÷ ይህንኑ ፡ ፍርድ ፡ ያድርጉበት ።
፴፪ በሬው ፡ ወንድ ፡ ባሪያ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ባሪያ ፡
ቢወጋ ÷ የበሬው ፡ ባለቤት ፡ ሠላሳ ፡ የብር ፡
ሰቅል ፡ ለጌታቸው ፡ ይስጥ ÷ በሬውም ፡ ይወ
ገር ።
፴፫ ሰውም ፡ ጕድጓድ ፡ ቢከፍት ÷ ወይም ፡ ጕድ
ጓድ ፡ ቢቈፍር ፡ ባይከድነውም ÷ በሬም ፡ ወይም ፡
፴፬ አህያ ፡ ቢወድቅበት ÷ የጕድጓዱ ፡ ባለቤት ፡
ዋጋቸውን ፡ ለባለቤታቸው ፡ ይክፈል ፤ የሞተ
ውም ፡ ለእርሱ ፡ ይሁን ።
፴፭ የሰው ፡ በሬ ፡ የሌላውን ፡ በሬ ፡ እስኪሞት ፡
ድረስ ፡ ቢወጋ ÷ ደኅናውን ፡ በሬ ፡ ይሽጡ ÷ ዋጋ
ውንም ፡ በትክክል ፡ ይክፈሉ ፤ የሞተውንም ፡
፴፮ ደግሞ ፡ በትክክል ፡ ይክፈሉ ። በሬውም ፡ አስ
ቀድሞ ፡ ተዋጊ ፡ መሆኑ ፡ ቢታወቅ ÷ ባለቤ
ቱም ፡ ባይጠብቀው ÷ በሬውን ፡ በበሬው ፡
ፋንታ ፡ ይስጥ ÷ የሞተውም ፡ ለእርሱ ፡ ይሁነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ ሰው ፡ በሬ ፡ ወይም ፡ በግ ፡ ቢሰርቅ ÷ ቢያር
ደው ፡ ወይም ፡ ቢሸጠው ÷ በበሬው ፡ ፋንታ ፡
አምስት ፡ በሬዎች ÷ በበጉም ፡ ፋንታ ፡ አራት ፡
፪ በጎች ፡ ይክፈል ። ሌባው ፡ ቤት ፡ ሲምስ ፡ ቢገኝ ÷
እርሱም ፡ እስኪሞት ፡ ቢመታ ÷ በመታው ፡
፫ ሰው ፡ ላይ ፡ የደም ፡ ዕዳ ፡ አይሆንበትም ። ፀሐይ ፡
ግን ፡ ከወጣችበት ፡ የደም ፡ ዕዳ ፡ አለበት ፤
ሌባው ፡ የሰረቀውን ፡ ይመልስ ፤ የሚከፍለ
፬ ውም ፡ ቢያጣ ፡ ስለ ፡ ስረቀው ፡ ይሸጥ ። የስረ
ቀው ፡ ደኅና ፡ ሆኖ ፡ በእጁ ፡ ቢገኝ ÷ በሬም ፡
ወይም ፡ አህያ ፡ ወይም ፡ በግ ፡ ቢሆን ÷ የስረቀ
ውን ፡ ያህል ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ ይክፈል ።
፭ ማንም ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ እርሻ ፡ ወይም ፡ ወደ ፡
ወይን ፡ ስፍራ ፡ ከብቱን ፡ ቢነዳው ÷ የሌላው
ንም ፡ እርሻ ፡ ቢያስበላ ÷ ከተመረጠ ፡ እርሻው ፡
ከማስፈያውም ፡ ወይኑ ፡ ይካስ ።
፮ እሳት ፡ ቢነሣ ÷ እሾኽንም ፡ ቢይዝ ÷ ክምሩ
ንም ፡ ወይም ፡ ያልታጨደውን ፡ እህል ፡ ወይም ፡
እርሻውን ፡ ቢያቃጥል ÷ እሳቱን ፡ ያነደደው ፡
ይካስ ።
፯ ሰው ፡ በባልንጀራው ፡ ዘንድ ፡ ብር ፡ ወይም ፡
ሌላ ፡ ነገር ፡ እንዲጠብቅለት ፡ አደራ ፡ ቢያኖር ፡
ከቤቱም ፡ ቢሰረቅ ÷ ሌባው ፡ ቢገኝ ፡ ስለ ፡ አንድ ፡
፰ ሁለት ፡ ይክፈል ። ሌባውም ፡ ባይገኝ ፡ ባለቤቱ ፡
ወደ ፡ ፈራጆች ፡ ይቅረብ ÷ እጁንም ፡ በባልንጀ
ራው ፡ ከብት ፡ ላይ ፡ እንዳልዘረጋ ፡ ይማል ።
፱ ሰዎች ፡ ስለ ፡ በሬ ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አህያ ፡ ወይም ፡
ስለ ፡ በግ ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ ልብስ ፡ ወይም ፡ ስለ ፡
ሌላ ፡ ስለ ፡ ጠፋ ፡ ነገር ፡ ቢካሰሱ ÷ አንዱም ፡—
ይህ ፡ የእኔ ፡ ነው ፡ ቢል ÷ ክርክራቸው ፡ ወደ ፡ ፈራ
ጆች ፡ ይድረስ ፤ ፈራጆቹም ፡ የፈረዱበት ፡ እርሱ ፡
ለባልንጀራው ፡ በአንድ ፡ ሁለት ፡ ይክፈል ።
፲ ሰው ፡ በባልንጀራው ፡ ዘንድ ፡ አህያ ፡ ወይም ፡
በሬ ፡ ወይም ፡ በግ ፡ ወይም ፡ ሌላ ፡ እንስሳ ፡
እንዲጠብቅለት ፡ አደራ ፡ ቢያኖር ÷ ማንም ፡
ሳያይ ፡ ቢሞት ፡ ወይም ፡ ቢጐዳ ፡ ወይም ፡ ቢማ
፲፩ ረክ ÷ በባልንጀራው ፡ ከብት ፡ ላይ ፡ እጁን ፡
እንዳልዘረጋ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መሐላ ፡ በሁለ
ታቸው ፡ መካከል ፡ ይሁን ፤ የከብቱም ፡ ባለቤት ፡
መሐላውን ፡ ይቀበል ÷ እርሱም ፡ ምንም ፡ አይክ
፲፪ ፈል ። ከእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ቢሰረቅ ፡ የጠፋውን ፡
፲፫ ያህል ፡ ለባለቤቱ ፡ ይመልስ ። ተቧጭሮም ፡
ቢገኝ ፡ ለምስክር ፡ ያምጣው ፤ በመቧጨሩም ፡
ምክንያት ፡ አይክፈል ።
፲፬ ከባልንጀራው ፡ እንዳች ፡ ቢዋስ ፡ ባለቤቱ ፡ ከእ
ርሱ ፡ ጋር ፡ ሳይኖር ፡ ቢጐዳ ÷ ወይም ፡ ቢሞት ÷
፲፭ ፈጽሞ ፡ ይክፈለው ። ባለቤቱ ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡
ጋር ፡ ቢኖር ፡ አይክፈል ፤ ቢከራየው ፡ በኪራዩ ፡
ይግባ ።

፲፮ ሰው ፡ ያልታጨችውን ፡ ድንግል ፡ ቢያስታት ፥ ከእርስዋም ፡ ጋር ፡ ቢተኛ ፥ ማጫዋን ፡ ሰጥቶ ፡ ሚስት ፡ ያድርጋት ። ፲፯ አባትዋም ፡ እርስዋን ፡ እንዳይሰጠው ፡ ፈጽሞ ፡ እንቢ ፡ ቢል ፡ እንደ ፡ ደናግል ፡ ማጫ ፡ ያህል ፡ ብር ፡ ይክፈላት ።

፲፰ መተተኛይቱን ፡ በሕይወት ፡ እንድትኖር ፡ አትፍቀድላት ።

፲፱ ከእንስሳ ፡ ጋር ፡ የሚረክስ ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደል ። ፳ ከእግዚአብሔር ፡ በቀር ፡ ለአንዳች ፡ አምላክ ፡ የሚሠዋ ፡ ፈጽሞ ፡ ይጥፋ ። ፳፩ እናንተ ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ስደተኞች ፡ ነበራችሁና ፡ ስደተኛውን ፡ አትበድለው ፥ ግፍም ፡ አታድርግበት ። ፳፪ መበለቲቱንና ፡ ድሀ ፡ አደጎቹን ፡ አታስጨንቁአቸው ። ፳፫ ብታስጨንቁአቸውና ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ቢጮኹ ፡ እኔ ፡ ጩኸታቸውን ፡ ፈጽሞ ፡ እሰማለሁ ፤ ፳፬ ቍጣዬም ፡ ይጸናባችኋል ፥ በሰይፍም ፡ እስገድላች ኋለሁ ፤ ሚስቶቻችሁም ፡ መበለት ፥ ልጆቻች ሁም ፡ ድሀ ፡ አደጎች ፡ ይሆናሉ ።

፳፭ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ስተቀመጠው ፡ ስወገኔ ፡ ስድ ህው ፡ ገንዘብ ፡ ብታበድረው ፥ እንደ ፡ በስ ፡ አራጣ ፡ አትሁን ፥ አራጣም ፡ አትጫንበት ። ፳፮ የባልንጀራህን ፡ ልብስ ፡ ለመያዣ ፡ ብትወስድ ፡ ፳፯ ፀሐይ ፡ ሳትገባ ፡ መልስለት ፤ ሥጋውን ፡ የሚከ ድንበት ፡ እርሱ ፡ ብቻ ፡ ነውና ፤ የሚተኛበ ትም ፡ ሌላ ፡ የለውምና ፤ ወደ ፡ እኔም ፡ ቢጮኽ ፡ መሐሪ ፡ ነኝና ፡ እሰማዋለሁ ።

፳፰ ፈራጆችን ፡ አትሰደብ ፥ የሕዝብህንም ፡ አለቃ ፡ ፳፱ አትርገመው ። ነዶህንም ፡ የወይንህንም ፡ ጭማቂ ፡ ለማቅረብ ፡ አትዘግይ ፤ የልጆችህ ፴ ንም ፡ በኵር ፡ ትሰጠኛለህ ። እንዲህም ፡ በበ ሬዎችህና ፡ በበጎችህ ፡ ታደርገዋለህ ፤ ሰባት ፡ ቀን ፡ ከእናቱ ፡ ጋር ፡ ይቀመጥ ፥ በስምንተኛ ፴፩ ውም ፡ ቀን ፡ ለእኔ ፡ ትሰጠዋለህ ። ቅዱስ ፡ ወገን ፡ ትሆኑልኛላችሁ ፤ ስለዚህ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ አውሬ ፡ የቧጨረውን ፡ ሥጋ ፡ ለውሾች ፡ ጣሉት ፡ እንጂ ፡ አትብሉት ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ ሐሰተኛ ፡ ወሬ ፡ አትቀበል ፤ ሐሰተኛ ፡ ምስ ክርም ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ከኃጢአተኛ ፡ ጋር ፡ ፪ እጅህን ፡ አታንሣ ። ከፉውን ፡ ለማድረግ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ አትከተል ፤ ፍርድንም ፡ ለማ ጣመም ፡ ከብዙ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ተስማምተህ ፡ ፫ አትመስክር ። በፍርድ ፡ ነገርም ፡ ለድሀው ፡ አታድላ ።

፬ የጠላትህን ፡ በሬ ፡ ወይም ፡ አህያውን ፡ ጠፍቶ ፡ ፭ ብታገኘው ፡ በፍጹም ፡ መልስለት ። የሚጠላ ህን ፡ ሰው ፡ አህያ ፡ ከሸክሙ ፡ በታች ፡ ወድቆ ፡ ብታየው ፡ አትተወው ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አንሣው ።

፮ በሚምዋገትበት ፡ ጊዜ ፡ የድሀህን ፡ ፍርድ ፡ ፯ አታጣምም ። ከሐሰት ፡ ነገር ፡ ራቅ ፤ እኔ ፡ ኃጢአተኛውን ፡ አላጸድቅምና ፡ ንጹሕንና ፡ ፰ ጻድቅን ፡ አትግደል ። ማማለጃን ፡ አትቀበል ፤ ማማለጃ ፡ የዓይናማዎችን ፡ ሰዎች ፡ ዓይን ፡ ያሳ ውራልና ፥ የጻድቃንንም ፡ ቃል ፡ ያጣምማልና ። ፱ ለስደተኛው ፡ ግፍ ፡ አታድርጉ ፤ እናንተ ፡ በግ ብፅ ፡ ምድር ፡ ስደተኞች ፡ ስለ ፡ ነበራችሁ ፡ የስ ደተኛ ፡ ነፍስ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ እው ቃችኋልና ።

፲ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ምድርህን ፡ ዝራ ፥ ፍሬዋ ፲፩ ንም ፡ አግባ ፤ በሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ ግን ፡ ተዋት ፡ አሳርፋትም ፤ የሕዝብህም ፡ ድሆች ፡ ይበሉታል ፤ ያስቀሩትንም ፡ የሜዳ ፡ እንስሳ ፡ ይብላው ። እንዲሁም ፡ በወይንህና ፡ በወይራህ ፡ ፲፪ አድርግ ። ስድስት ፡ ቀን ፡ ሥራህን ፡ ሥራ ፤ በሬህና ፡ አህያህ ፡ ያርፉ ፡ ዘንድ ፡ ሰበሪያህም ፡ ልጅ ፡ ስመጻተኛውም ፡ ዕረፍት ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ፲፫ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ዕረፍ ። ያልኋችሁንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ጠብቁ ፤ የሌሎችንም ፡ አማልክት ፡ ስም ፡ አትጥሩ ፥ ከአፋችሁም ፡ አይሰማ ።

፲፬ በዓመት ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ በዓል ፡ ታደርግል ፲፭ ኛለህ ። የቂጣውን ፡ በዓል ፡ ጠብቅ ፤ በአቢብ ፡ ወር ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ወጥታችኋልና ፡ በዚህ ፡ ወር ፡ እንዳዘዝሁህ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ቂጣ ፡ እንጀራ ፡ ትበላለህ ፤ በፊቴም ፡ ባዶ ፡ እጃችሁን ፡ አትታዩ ። ፲፮ በእርሻም ፡ የምትዘራትን ፡ የፍሬህን ፡ በኩራት ፡ የመከር ፡ በዓል ፥ ዓመቱም ፡ ሳያልቅ ፡ ፍሬህን ፡ ከእርሻ ፡ በከማቸህ ፡ ጊዜ ፡ የመከተቻውን ፡ ፲፯ በዓል ፡ ጠብቅ ። በዓመት ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ በአ ንተ ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ በጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይታይ ።

፲፰ የመሥዋዕቴን ፡ ደም ፡ ከቦካ ፡ እንጀራ ፡ ጋር ፡ አትሠዋ ፤ የበዓሌም ፡ ስብ ፡ እስከ ፡ ነጋ ፡ አይደር ። ፲፱ የተመረጠውን ፡ የምድርህን ፡ ፍሬ ፡ በኵራት ፡ ወደ ፡ አምላክህ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አምጣ ። ጠቦትን ፡ በእናቱ ፡ ወተት ፡ አትቀ ቅል ።

፳ በመንገድ ፡ ይጠብቅህ ፡ ዘንድ ፡ ወዳዘጋጀሁ ትም ፡ ስፍራ ፡ ያገባህ ፡ ዘንድ ፥ እነሆ ፥ እኔ ፡ ፳፩ መልአክን ፡ በፊትህ ፡ እሰድዳለሁ ። በፊቱ ፡ ተጠ ንቀቁ ፥ ቃሉንም ፡ አድምጡ ፤ ስሜም ፡ በእ ርሱ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ኃጢአት ፡ ብትሠሩ ፡ ይቅር ፡ ፳፪ አይልምና ፡ አታስመርሩት ። አንተ ፡ ግን ፡ ቃሉን ፡ ብትሰማ ፥ ያልሁህንም ፡ ሁሉ ፡ ብታደ ርግ ፥ ጠላቶችህን ፡ እጣላቸዋለሁ ፥ የሚያስጨ ፳፫ ንቁህንም ፡ እስጨንቃቸዋለሁ ። መልአኬ ፡ በፊትህ ፡ ይሄዳልና ፥ ወደ ፡ አሞራውያንም ፡ ወደ ፡ ኬጢያውያንም ፡ ወደ ፡ ፌርዛውያንም ፡ ወደ ፡ ከነዓናውያንም ፡ ወደ ፡ ኤዊያውያንም ፡ ወደ ፡ ኢያቡሳውያንም ፡ ያገባሃል ፤ እኔም ፡ ፳፬ አጠፋቸዋለሁ ። ለአማልክቶቻቸው ፡ አትስ ገድ ፥ አታምልካቸውም ፤ እንደ ፡ ሥራቸውም ፡ አትሥራ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ፈጽመህ ፡ አፍርሳቸው ፥ ፳፭ ሐውልቶቻቸውንም ፡ ሰባብራቸው ። አምላ ካችሁንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ታመልኩታላ ችሁ ፥ እርሱም ፡ እህልህንና ፡ ውኃህን ፡ ይባር ካል ፤ በሽታንም ፡ ከመካከልህ ፡ አርቃለሁ ።

፳፮ በምድርህም ፡ መካን ፡ ወይም ፡ የምትጨነግፍ ፡
አትሆንም ፤ የዘመንህን ፡ ቍጥር ፡ እሞላለሁ ።
፳፯ መፈራቴንም ፡ በፊትህ ፡ እሰድዳለሁ ÷ የምትሄድ
በትንም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ እስደነግጣቸዋለሁ ÷
ጠላቶችህንም ፡ ሁሉ ፡ በፊትህ ፡ ጀርባቸውን ፡ እን
፳፰ ዲያዞሩ ፡ አደርጋለሁ ። በፊትህም ፡ ተርብ ፡ እሰድ
ዳለሁ ÷ ኤዊያዊውንም ፡ ከነዓናዊውንም ፡ ኬጢ
፳፱ ያዊውንም ፡ ከፊትህ ፡ አባርራለሁ ። ምድር ፡
ባድማ ፡ እንዳትሆን ÷ የምድር ፡ አራዊትም ፡
እንዳይበዙብህ ÷ በአንድ ፡ ዓመት ፡ ከፊታችሁ ፡
፴ አላባርራቸውም ። ነገር ፡ ግን ፡ እስክትበዛ ፡
ምድርንም ፡ እስክትወርስ ፡ ድረስ ፡ በጥቂት ፡
፴፩ በጥቂት ፡ አባርራቸዋለሁ ። ድንበርህንም ፡
ከኤርትራ ፡ ባሕር ፡ እስከ ፡ ፍልስጥኤም ፡ ባሕር ÷
ከምድረ ፡ በዳም ፡ እስከ ፡ ወንዙ ፡ ድረስ ፡ አደ
ርጋለሁ ፤ በምድር ፡ የሚኖሩትን ፡ በእጅህ ፡
እጥላለሁና ፤ ከፊትህም ፡ ታባርራቸዋለህ ።
፴፪ ከእነርሱና ፡ ከአማልክቶቻቸው ፡ ጋር ፡ ቃል ፡
፴፫ ኪዳን ፡ አታድርግ ። አማልክቶቻቸውንም ፡
ብታመልክ ፡ ወጥመድ ፡ ይሆኑብሃልና ፡ እኔን ፡
እንድትበድል ፡ እንዳያደርጉህ ፡ በአገርህ ፡ አይ
ቀመጡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ ሙሴንም ፡— አንተ ፡ አሮንም ፡ ናዳብም ፡
አብዩድም ፡ ከእስራኤልም ፡ ሰባ ፡ ሽማግሌዎች ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ውጡ ÷ በሩቁም ፡ ስገዱ ፤
፪ ሙሴም ፡ ብቻውን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቅ
ረብ ÷ እነርሱ ፡ ግን ፡ አይቅረቡ ፤ ሕዝቡም ፡ ከእ
፫ ርሱ ፡ ጋር ፡ አይውጡ ፡ አለው ። ሙሴም ፡
መጣ ፡ ለሕዝቡም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃሎች ፡
ሁሉ ፡ ሥርዓቱንም ፡ ሁሉ ፡ ነገረ ፤ ሕዝቡም ፡
ሁሉ ፡ በአንድ ፡ ድምፅ ፡— እግዚአብሔር ፡ የተ
ናገራቸውን ፡ ቃሎች ፡ ሁሉ ፡ እናደርጋለን ፡
፬ ብለው ፡ መለሱ ። ሙሴም ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ቃሎች ፡ ጻፈ ፤ ማለዳም ፡ ተነሣ ÷ ከተራራ
ውም ፡ በታች ፡ መሠዊያን ÷ አሥራ ፡ ሁለትም ፡
ሐውልቶች ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ የእስራኤል ፡
፭ ነገድ ፡ ሠራ ። የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ እን
ዲያቀርቡ ÷ ለእግዚአብሔርም ፡ ስለ ፡ ደኅንነት ፡
መሥዋዕት ፡ በሬዎችን ፡ እንዲሠዉ ፡ የእስራኤ
፮ ልን ፡ ልጆች ፡ ጐበዛዝት ፡ ሰደደ ። ሙሴም ፡
የደሙን ፡ እኩሌታ ፡ ወስዶ ፡ በቆሬ ፡ ውስጥ ፡
አኖረው ፤ የደሙንም ፡ እኩሌታ ፡ በመሠዊ
፯ ያው ፡ ረጨው ። የቃል ፡ ኪዳኑንም ፡ መጽሐፍ ፡
ወስዶ ፡ ለሕዝቡ ፡ አነበበላቸው ፤ እነርሱም ፡—
እግዚአብሔር ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ እናደርጋለን ፡ እን
፰ ታዘዛለንም ፡ አሉ ። ሙሴም ፡ ደሙን ፡ ወስዶ ፡
በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ረጨው ፡— በዚህ ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡
እግዚአብሔር ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ያደረገው ፡
የቃል ፡ ኪዳኑ ፡ ደም ፡ እነሆ ፡ አለ ።
፱ ሙሴም ፡ አሮንም ፡ ናዳብም ፡ አብዩድም ፡ ከእ
፲ ስራኤልም ፡ ሰባ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ወጡ ፤ የእስ
ራኤልንም ፡ አምላክ ፡ አዩ ፤ ከእግሩም ፡ በታች ፡
እንደ ፡ ሰማይ ፡ መልክ ፡ የሚያበራ ፡ እንደ ፡
ብሩህ ፡ ሰንፔር ፡ ድንጋይ ፡ የሚመስል ፡ ወለል ፡
፲፩ ነበረ ። እጁንም ፡ በእስራኤል ፡ አዛውንቶች ፡
ላይ ፡ አልዘረጋም ፤ እነርሱም ፡ እግዚአብሔርን ፡
አዩ ÷ በሉም ፡ ጠጡም ።
፲፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— ወደ ፡ እኔ ፡ ወደ ፡
ተራራው ፡ ውጣ ÷ በዚያም ፡ ሁን ፤ እነርሱን ፡
ታስተምር ፡ ዘንድ ፡ እኔ ፡ የጻፍሁትን ፡ ሕግና ፡ ትእ
ዛዝ ፡ የድንጋይም ፡ ጽላት ፡ እሰጥሃለሁ ፡ አለው ።
፲፫ ሙሴና ፡ ሎሌው ፡ ኢያሱ ፡ ተነሡ ፤ ሙሴም ፡
፲፬ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተራራ ፡ ወጣ ። ሽማግ
ሌዎችንም ፡— ወደ ፡ እናንተ ፡ እስክንመለስ ፡
ድረስ ፡ በዚህ ፡ ቆዩን ፤ አሮንና ፡ ሖርም ፡ እነሆ ፡
ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ናቸው ÷ ነገረተኛም ፡ ቢኖር ፡
፲፭ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ይምጣ ፡ አላቸው ። ሙሴም ፡
ወደ ፡ ተራራ ፡ ወጣ ÷ ደመናውም ፡ ተራራውን ፡
፲፮ ሸፈነው ። የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ በሲና ፡
ተራራ ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ÷ ደመናውም ፡ ስድስት ፡
ቀን ፡ ሸፈነው ፤ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ ከደመናው ፡
፲፯ ውስጥ ፡ ሙሴን ፡ ጠራው ። በተራራው ፡ ራስ ፡
ላይ ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ ክብር ፡ መታየት ፡ እንደሚያቃጥል ፡ እሳት ፡
፲፰ ነበረ ። ሙሴም ፡ ወደ ፡ ደመናው ፡ ውስጥ ፡ ገባ ፡
ወደ ፡ ተራራውም ፡ ወጣ ፤ ሙሴም ፡ በተራራው ፡
ላይ ፡ አርባ ፡ ቀን ፡ አርባ ፡ ሌሊትም ፡ ቆየ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ተና
፪ ገረው ፡— ስጦታ ፡ ያመጡልኝ ፡ ዘንድ ፡ ለእ
ስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተናገር ፤ በገዛ ፡ እጁ ፡ ሊሰ
ጠኝ ፡ በልቡ ፡ ከሚያምረው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡
፫ መባ ፡ ተቀበሉ ። ከእነርሱም ፡ የምትቀበሉት ፡
፬ መባ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ወርቅ ÷ ብር ÷ ናስም ÷ ሰማ
ያዊና ፡ ሐምራዊ ፡ ቀይም ፡ ግምጃ ÷ ጥሩ ፡ በፍ
፭ ታም ÷ የፍየልም ፡ ጠጕር ÷ ቀይ ፡ የአውራ ፡
በግ ፡ ቁርበት ÷ የአቆስጣ ፡ ቁርበት ÷ የግራ
፮ ርም ፡ እንጨት ÷ የመብራትም ፡ ዘይት ÷ ለቅ
ብዓት ፡ ዘይትና ፡ ለጣፋጭ ፡ ዕጣን ፡ ቅመም ÷
፯ መረግድም ÷ ለኤፉድና ፡ ለደረት ፡ ኪስ ፡ የሚ
፰ ደረግ ፡ ፈርጥ ። በመካከላቸውም ፡ አድር ፡
፱ ዘንድ ፡ መቅደስ ፡ ይሥሩልኝ ። እኔ ፡ እንደማሳ
ይህ ፡ ሁሉ ÷ እንደ ፡ ማደሪያው ፡ ምሳሌ ፡ እንደ ፡
ዕቃውም ፡ ሁሉ ፡ ምሳሌ ÷ እንዲሁ ፡ ሥሩት ።
፲ ከግራር ፡ እንጨትም ፡ ታቦትን ፡ ይሥሩ ፤ ርዝ
መቱ ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፡ ተኩል ÷ ወርዱም ፡
አንድ ፡ ክንድ ፡ ተኩል ÷ ቁመቱም ፡ አንድ ፡
፲፩ ክንድ ፡ ተኩል ፡ ይሁን ። በውስጥና ፡ በው
ጭም ፡ በጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ለብጠው ፤ በእርሱም ፡
ላይ ፡ በዙሪያው ፡ የወርቅ ፡ አክሊል ፡ አድ
፲፪ ርግለት ። አራት ፡ የወርቅ ፡ ቀለበቶችም ፡
አድርግለት ÷ እነርሱንም ፡ በአራቱ ፡ እግሮቹ ፡
ላይ ፡ አኑር ፤ በአንድ ፡ ወገን ፡ ሁለት ፡ ቀለ
በቶች ÷ በሌላው ፡ ወገን ፡ ሁለት ፡ ቀለበቶች ፡
፲፫ ይሁኑ ። መሎጊያዎችንም ፡ ከግራር ፡ እን

፲፬ ጨት ፡ ሥራ ፥ በወርቅም ፡ ለብጣቸው ። ለታ
ቦቱ ፡ መሸከሚያ ፡ በታቦቱ ፡ ጐን ፡ ባሉት ፡ ቀለ
፲፭ በቶች ፡ መሎጊያዎቹን ፡ አግባ ። መሎጊያዎ
ቹም ፡ በታቦቱ ፡ ቀለበቶች ፡ ውስጥ ፡ ይኑሩ ፥
፲፮ ከቶም ፡ አይውጡ ። በታቦቱም ፡ ውስጥ ፡ እኔ ፡
፲፯ የምሰጥህን ፡ ምስክር ፡ ታስቀምጣለህ ። ከጥሩ ፡
ወርቅም ፡ ርዝመቱ ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፡ ተኩል ፥
ወርዱም ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ተኩል ፡ የሆነ ፡
፲፰ የስርየት ፡ መክደኛ ፡ ሥራ ። ሁለት ፡ ኪሩቤል ፡
ከተቀጠቀጠ ፡ ወርቅ ፡ ሥራ ፥ በስርየት ፡ መክ
ደኛውም ፡ ላይ ፡ በሁለት ፡ ወገን ፡ ታደርጋቸዋ
፲፱ ለህ ። ከስርየት ፡ መክደኛውም ፡ ጋር ፡ አንዱን ፡
ኪሩብ ፡ በአንድ ፡ ወገን ፥ ሁለተኛውንም ፡
ኪሩብ ፡ በሌላው ፡ ወገን ፡ አድርገህ ፡ በአንድ ፡
፳ ላይ ፡ ትሠራዋለህ ። ኪሩቤልም ፡ ክንፎቻቸ
ውን ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ይዘረጋሉ ፥ የስርየት ፡ መክ
ደኛውንም ፡ በክንፎቻቸው ፡ ይሸፍናሉ ፥ ፊታ
ቸውም ፡ እርስ ፡ በርሱ ፡ ይተያያል ፤ የኪሩቤ
ልም ፡ ፊቶቻቸው ፡ ወደ ፡ ስርየት ፡ መክደኛው ፡
፳፩ ይመለከታሉ ። የስርየት ፡ መክደኛውንም ፡
በታቦቱ ፡ ላይ ፡ ታደርገዋለህ ፤ እኔም ፡ የምሰጥ
ህን ፡ ምስክር ፡ በታቦቱ ፡ ውስጥ ፡ ታኖረዋለህ ።
፳፪ በዚያም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ እገናኛለሁ ፤ የእስራ
ኤልንም ፡ ልጆች ፡ ታዝዝ ፡ ዘንድ ፡ የምሰጥ
ህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፥ በምስክሩ ፡ ታቦት ፡ ላይ ፡
ባለው ፡ በሁለት ፡ ኪሩቤል ፡ መካከል ፥ በስር
የት ፡ መክደኛውም ፡ ላይ ፡ ሆኜ ፡ እነጋገር
ሃለሁ ።
፳፫ ርዝመቱም ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፥ ወርዱም ፡ አንድ ፡
ክንድ ፥ ቁመቱ ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ተኩል ፡ የሆነ ፡
፳፬ ገበታ ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ ሥራ ። በጥሩም ፡
ወርቅ ፡ ትለብጠዋለህ ፤ በዙሪያውም ፡ የወርቅ ፡
፳፭ አክሊል ፡ አድርግለት ፤ በዙሪያውም ፡ አንድ ፡
ጋት ፡ የሚያህል ፡ ክፈፍ ፡ አድርግለት ፤ የወር
ቅም ፡ አክሊል ፡ በክፈፉ ፡ ዙሪያ ፡ አድርግለት ።
፳፮ አራትም ፡ የወርቅ ፡ ቀለበቶች ፡ አድርግለት ፤
ቀለበቶቹንም ፡ አራቱ ፡ እግሮቹ ፡ ባሉበት ፡
፳፯ በአራቱ ፡ ማዕዘኖች ፡ አድርግ ። ገበታውንም ፡
ለመሸከም ፡ መሎጊያዎቹ ፡ እንዲሰኩባቸው ፡
፳፰ ቀለበቶቹ ፡ በክፈፉ ፡ አቅራቢያ ፡ ይሁኑ ። ገበ
ታውን ፡ ይሸከሙባቸው ፡ ዘንድ ፡ መሎጊያዎ
ቹን ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ ሥርተህ ፡ በወርቅ ፡
፳፱ ለብጣቸው ። ሰማፍሰሻም ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡
ወጭቶችዋን ፡ ጭልፋዎችዋንም ፡ መቅጃዎች
ዋንም ፡ ጽዋዎችዋንም ፡ አድርግ ፤ እነርሱንም ፡
፴ ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ አድርጋቸው ። በገበታም ፡ ላይ ፡
የገጽ ፡ ኅብስት ፡ ሁልጊዜ ፡ በፊቴ ፡ ታደርጋለህ ።
፴፩ መቅረዝንም ፡ ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ አድርግ ፤ መቅ
ረዙ ፡ ከእግሩና ፡ ከአገዳው ፡ ጋር ፡ በተቀጠቀጠ ፡
ሥራ ፡ ይደረግ ፤ ጽዋዎቹም ፡ ጕብጕቦቹም ፡ አበ
፴፪ ቦቹም ፡ አንድነት ፡ በእርሱ ፡ ይደረጉበት ። በስተ ፡
ጎኑ ፡ ስድስት ፡ ቅርንጫፎች ፡ ይውጡለት ፤
ሦስት ፡ የመቅረዙ ፡ ቅርንጫፎች ፡ በአንድ ፡ ወገን ፥
ሦስትም ፡ የመቅረዙ ፡ ቅርንጫፎች ፡ በሌላ ፡
ወገን ፡ ይውጡ ። በአንደኛውም ፡ ቅርንጫፍ ፡ ፴፫
ጕብጕብና ፡ አበባ ፡ ሦስትም ፡ የለውዝ ፡ አበባ ፡
የሚመስሉትን ፡ ጽዋዎች ፥ በሁለተኛውም ፡
ቅርንጫፍ ፡ ጕብጕብና ፡ አበባ ፡ ሦስትም ፡ የለ
ውዝ ፡ አበባ ፡ የሚመስሉትን ፡ ጽዋዎች ፤ እን
ዲሁም ፡ ከመቅረዙ ፡ ለሚወጡ ፡ ለስድስቱ ፡
ቅርንጫፎች ፡ አድርግ ። በመቅረዙም ፡ ጕብጕ ፴፬
ቦቹንና ፡ አበቦቹን ፡ አራትም ፡ የለውዝ ፡ አበባ ፡
የሚመስሉትን ፡ ጽዋዎች ፡ አድርግ ። ከመቅ ፴፭
ረዙ ፡ ለሚወጡ ፡ ለስድስቱ ፡ ቅርንጫፎች ፡ ከሁ
ለት ፡ ቅርንጫፎች ፡ በታች ፡ አንድ ፡ ሆኖ ፡ የተ
ሠራ ፡ አንድ ፡ ጕብጕብ ፥ ከሁለትም ፡ ቅርንጫ
ፎች ፡ በታች ፡ አንድ ፡ ሆኖ ፡ የተሠራ ፡ አንድ ፡
ጕብጕብ ፥ ደግሞ ፡ ከሁለት ፡ ቅርንጫፎች ፡
በታች ፡ አንድ ፡ ሆኖ ፡ የተሠራ ፡ አንድ ፡ ጕብ
ጕብ ፡ ይሁን ። ጕብጕቦቹና ፡ ቅርንጫፎቹ ፡ ሁሉ ፡ ፴፮
ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ይሁኑ ፤ ሁሉም ፡ አንድ ፡
ሆኖ ፡ ከተቀረጸ ፡ ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ይደረግ ። ሰባ ፴፯
ቱንም ፡ መብራቶች ፡ ሥራ ፤ በፊቱ ፡ ያበሩ ፡
ዘንድ ፡ መብራቶቹን ፡ ያቀጣጥሉአቸዋል ። መኰ ፴፰
ስተሪያዎችዋን ፡ የኵስታሪ ፡ ማድረጊያዎችዋ
ንም ፡ ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ አድርግ ። መቅረዙም ፡ ፴፱
ዕቃውም ፡ ሁሉ ፡ ከአንድ ፡ መክሊት ፡ ጥሩ ፡
ወርቅ ፡ ይሠሩ ። በተራራ ፡ ላይ ፡ እንዳሳየሁህ ፡ ፵
ምሳሌ ፡ እንድትሠራ ፡ ተጠንቀቅ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

ደግሞም ፡ ከተፈተለ ፡ ከጥሩ ፡ በፍታ ፥ ከሰ ፩
ማያዊ ፡ ከሐምራዊም ፡ ከቀይም ፡ ግምጃ ፡ የተ
ሠሩ ፡ አሥር ፡ መጋረጆች ፡ ያሉበትን ፡ ማደሪያ ፡
ሥራ ፤ ብልሀ ፡ ሠራተኛ ፡ እንደሚሠራ ፡ ኪሩ
ቤል ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ይሁኑ ። የእያንዳንዱ ፡ ፪
መጋረጃ ፡ ርዝመት ፡ ሀያ ፡ ስምንት ፡ ክንድ ፥
ወርዱም ፡ አራት ፡ ክንድ ፡ ይሁን ፤ የመጋረጆቹ ፡
ሁሉ ፡ መጠን ፡ ትክክል ፡ ይሁን ። አምስቱ ፡ ፫
መጋረጆች ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ የተጋጠሙ ፡
ይሁኑ ፤ አምስቱም ፡ መጋረጆች ፡ እንዲሁ ፡
እርስ ፡ በርሳቸው ፡ የተጋጠሙ ፡ ይሁኑ ። ከሚ ፬
ጋጠሙት ፡ መጋረጆች ፡ በአንደኛው ፡ መጋረጃ ፡
ዘርፍ ፡ ላይ ፡ የሰማያዊውን ፡ ግምጃ ፡ ቀለበቶች ፡
አድርግ ፤ ደግሞ ፡ ከተጋጠሙት ፡ ከሌሎች ፡
በአንደኛው ፡ መጋረጃ ፡ ዘርፍ ፡ ላይ ፡ እንዲሁ ፡
አድርግ ። አምስ ፡ ቀለበቶችን ፡ በአንድ ፡ መጋ ፭
ረጃ ፡ አድርግ ፥ አምሳውንም ፡ ቀለበቶች ፡ በሁ
ለተኛው ፡ መጋረጃ ፡ ዘርፍ ፡ አድርግ ፤ ቀለበ
ቶቹ ፡ ሁሉ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡
ይሆናሉ ። አምሳ ፡ የወርቅ ፡ መያዣዎች ፡ ሥራ ፤ ፮
ማደሪያውንም ፡ አንድ ፡ እንዲሆን ፡ መጋረጆ
ችን ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ በመያዣዎች ፡ አጋጥ
ማቸው ።
ከማደሪያውም ፡ በላይ ፡ ለድንኳን ፡ የሚሆኑ ፡ ፯
መጋረጆች ፡ ከፍየል ፡ ጠጕር ፡ አድርግ ፤ አሥራ ፡
አንድ ፡ መጋረጆች ፡ ታደርጋለህ ። እያንዳን ፰
ዱም ፡ መጋረጃ ፡ ርዝመቱ ፡ ሠላሳ ፡ ክንድ ፥ እያ

ንዳንዱም ፡ መጋረጃ ፡ ወርዱ ፡ አራት ፡ ክንድ ፡ ይሁን ፤ የአሥራ ፡ አንዱም ፡ መጋረጆች ፡ መጠ ናቸው ፡ ትክክል ፡ ይሁን ። ፱ አምስቱ ፡ መጋረ ጆች ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡ ይጋጠሙ ፥ ስድስቱም ፡ መጋረጆች ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡ ይጋጠሙ ፤ ስድስተኛውም ፡ መጋረጃ ፡ በድን ኳኑ ፡ ፊት ፡ ይደረብ ። ፲ ከተጋጠሙት ፡ መጋረ ጆች ፡ በአንደኛው ፡ መጋረጃ ፡ ዘርፍ ፡ ላይ ፡ አምሳ ፡ ቀለበቶች ፡ አድርግ ፤ ደግሞ ፡ ከተጋጠ ሙት ፡ ከሌሎቹ ፡ በአንድኛው ፡ መጋረጃ ፡ ዘርፍ ፡ ላይ ፡ እንዲሁ ፡ አምሳ ፡ ቀለበቶች ፡ አድርግ ። ፲፩ አምሳም ፡ የናስ ፡ መያዣዎችን ፡ ሥራ ፥ መያዣ ዎችንም ፡ ወደ ፡ ቀለበቶች ፡ አግባቸው ፥ ድንኳ ኑም ፡ አንድ ፡ እንዲሆን ፡ አጋጥመው ። ፲፪ ከድ ንኳኑ ፡ መጋረጆች ፡ የቀረ ፡ ትርፍ ፡ ግማሽ ፡ መጋረጃ ፡ በማደሪያው ፡ ጀርባ ፡ ይንጠልጠል ። ፲፫ ማደሪያውን ፡ እንዲሸፍን ፡ ከርዝመቱ ፡ በአንድ ፡ ወገን ፡ አንድ ፡ ክንድ ፥ በአንድ ፡ ወገንም ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ከድንኳኑ ፡ መጋረጆች ፡ የቀረው ፡ ትርፍ ፡ በማደሪያው ፡ ውጭ ፡ በወዲህና ፡ በወዲያ ፡ ይን ጠልጠል ። ፲፬ ለድንኳኑም ፡ መደረቢያ ፡ ከቀይ ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ቁርበት ፥ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ሌላ ፡ መደረቢያ ፡ ከአቆስጣ ፡ ቁርበት ፡ አድርግ ።

፲፭ ለማደሪያውም ፡ የሚቆሙትን ፡ ሳንቆች ፡ ከግ ራር ፡ እንጨት ፡ አድርግ ። ፲፮ የሳንቃው ፡ ሁሉ ፡ ርዝመቱ ፡ አሥር ፡ ክንድ ፥ ወርዱም ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ተኩል ፡ ይሁን ። ፲፯ ለእያንዳንዱም ፡ ሳንቃ ፡ እንዲገጠሙ ፡ በአንዱ ፡ ላይ ፡ የሚያያይዙ ፡ ሁለት ፡ ማጋጠሚያዎች ፡ ይሁኑለት ፤ ለማደሪ ያው ፡ ሳንቆች ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ አድርግ ። ፲፰ ለማ ደሪያውም ፡ በደቡብ ፡ ወገን ፡ ሀያ ፡ ሳንቆችን ፡ አድርግ ። ፲፱ ከሀያውም ፡ ሳንቆች ፡ በታች ፡ አርባ ፡ የብር ፡ እግሮችን ፡ አድርግ ፤ ከእያንዳንዱ ፡ ሳንቃ ፡ በታች ፡ ለሁለት ፡ ማጋጠሚያዎች ፡ ሁለት ፡ እግሮች ፡ ይሁኑ ። ፳ ለማደሪያው ፡ ለሁ ለተኛው ፡ ወገን ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ሀያ ፡ ሳን ቆች ፥ ፳፩ ለእነርሱም ፡ አርባ ፡ የብር ፡ እግሮች ፡ ይሁኑ ፤ ከእያንዳንዱም ፡ ሳንቃ ፡ በታች ፡ ሁለት ፡ እግሮች ፡ ይሁኑ ። ፳፪ ለማደሪያውም ፡ በምዕራቡ ፡ ወገን ፡ በስተ ፡ ኋላ ፡ ስድስት ፡ ሳንቆችን ፡ አድርግ ። ፳፫ ለማደሪያውም ፡ ለሁለቱ ፡ ማዕዘን ፡ በስተ ፡ ኋላ ፡ ፳፬ ሁለት ፡ ሳንቆችን ፡ አድርግ ። ከታችም ፡ እስከ ፡ ላይ ፡ እስከ ፡ አንደኛው ፡ ቀለበት ፡ ድረስ ፡ አንዱ ፡ ሳንቃ ፡ ድርብ ፡ ይሁን ፤ እንዲሁም ፡ ለሁለቱ ፡ ይሁን ፤ እነርሱም ፡ ለሁለቱ ፡ ማዕዘን ፡ ይሆ ፳፭ ናሉ ። ስምንት ፡ ሳንቆችና ፡ አሥራ ፡ ስድስት ፡ የብር ፡ እግሮቻቸው ፡ ይሁኑ ፤ ከእያንዳንዱም ፡ ሳንቃ ፡ በታች ፡ ሁለት ፡ እግሮች ፡ ይሆናሉ ።

፳፮ ከግራርም ፡ እንጨት ፡ በማደሪያው ፡ በአንድ ፡ ወገን ፡ ላሉት ፡ ሳንቆች ፡ አምስት ፡ መወርወሪያ ፳፯ ዎች ፥ በማደሪያውም ፡ በሁለተኛው ፡ ወገን ፡ ላሉት ፡ ሳንቆች ፡ አምስት ፡ መወርወሪያዎች ፥ በማደሪያውም ፡ በስተ ፡ ኋላ ፡ በምዕራብ ፡ ወገን ፡ ላሉት ፡ ሳንቆች ፡ አምስት ፡ መወርወሪያዎች ፡ ፳፰ አድርግ ። መካከለኛውም ፡ መወርወሪያ ፡ በሳ ንቆች ፡ መካከል ፡ ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ ይለፍ ። ፳፱ ሳንቆቹንም ፡ በወርቅ ፡ ለብጣቸው ፤ ቀለበቶቻ ቸውንም ፡ የመወርወሪያ ፡ ቤት ፡ እንዲሆኑላ ቸው ፡ ከወርቅ ፡ ሥራቸው ፤ መወርወሪያዎች ንም ፡ በወርቅ ፡ ለብጣቸው ። ፴ ማደሪያውንም ፡ በተራራ ፡ እንዳሳየሁህ ፡ ምሳሌ ፡ አቁም ።

፴፩ መጋረጃውንም ፡ ከሰማያዊ ፡ ከሐምራዊም ፡ ከቀይም ፡ ግምጃ ፡ ከተፈተለ ፡ ከጥሩ ፡ በፍታም ፡ አድርግ ፤ ብልህ ፡ ሠራተኛ ፡ እንደሚሠራ ፡ ኪሩቤል ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ይሁኑ ። ፴፪ በወርቅ ፡ በተለበጡት ፡ ከግራር ፡ እንጨትም ፡ በተሠሩት ፡ በአራቱ ፡ ምሰሶች ፡ ላይ ፡ ስቀለው ፤ ኩላቦቻ ቸውም ፡ ከወርቅ ፥ አራቱም ፡ እግሮቻቸው ፡ ከብር ፡ የተሠሩ ፡ ይሁኑ ። ፴፫ መጋረጃውንም ፡ ከመያዣዎቹ ፡ በታች ፡ ታንጠለጥለዋለህ ፥ በመ ጋረጃውም ፡ ውስጥ ፡ የምስክርን ፡ ታቦት ፡ አግ ባው ፤ መጋረጃውም ፡ በቅድስቱና ፡ በቅድስተ ፡ ቅዱሳኑ ፡ መካከል ፡ መለያ ፡ ይሁናችሁ ። ፴፬ በቅ ድስተ ፡ ቅዱሳኑም ፡ ውስጥ ፡ የስርየት ፡ መክደ ኛውን ፡ በምስክሩ ፡ ታቦት ፡ ላይ ፡ አድርግ ። ፴፭ ገበታውንም ፡ በመጋረጃው ፡ ውጭ ፥ መቅ ረዙንም ፡ በገበታው ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በማደሪ ያው ፡ በደቡብ ፡ ወገን ፡ አድርግ ፤ ገበታውንም ፡ በሰሜን ፡ ወገን ፡ አድርገው ። ፴፮ ለድንኳኑም ፡ ደጃፍ ፡ ከሰማያዊ ፡ ከሐምራዊም ፡ ከቀይም ፡ ግምጃ ፡ ከተፈተለ ፡ ከጥሩ ፡ በፍታም ፡ በጥልፍ ፡ አሠራር ፡ የተሠራ ፡ መጋረጃ ፡ አድርግለት ። ፴፯ ለመጋረጃውም ፡ አምስት ፡ ምሰሶች ፡ ከግራር ፡ እን ጨት ፡ አድርግ ፥ በወርቅም ፡ ለብጣቸው ፤ ኩላ ቦቻቸውም ፡ ከወርቅ ፡ የተሠሩ ፡ ይሁኑ ፤ አም ስትም ፡ እግሮች ፡ አድርግላቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

፩ ርዝመቱ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፥ ወርዱም ፡ አም ስት ፡ ክንድ ፡ መሠዊያ ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ አድርግ ፤ አራት ፡ ማዕዘንም ፡ ይሁን ፤ ከፍታ ውም ፡ ሦስት ፡ ክንድ ፡ ይሁን ። ፪ በአራቱም ፡ ማዕዘን ፡ ቀንዶችን ፡ ታደርጋለህ ፥ ቀንዶቹም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በአንድ ፡ የተሠሩ ፡ ይሁኑ ፤ በና ስም ፡ ለብጠው ። ፫ አመድ ፡ የሚሆንባቸውን ፡ ምንቸቶች ፥ መጫሪያዎቹንም ፥ ድስቶቹንም ፥ ሜንጦቹንም ፥ ማንደጃዎቹንም ፡ አድርግ ፤ ዕቃ ውንም ፡ ሁሉ ፡ ከናስ ፡ አድርግ ። ፬ እንደ ፡ መረብ ፡ ሆኖ ፡ የተሠራ ፡ የናስ ፡ መከታ ፡ አድርግለት ፤ ለመከታውም ፡ አራት ፡ የናስ ፡ ቀለበት ፡ በአ ራቱ ፡ ማዕዘኑ ፡ አድርግለት ። ፭ መከታውም ፡ እስከ ፡ መሠዊያው ፡ እኩሌታ ፡ ይደርስ ፡ ዘንድ ፡ በመሠዊያው ፡ በሚዞረው ፡ በእርከኑ ፡ ታች ፡ አድ ርገው ። ፮ ለመሠዊያውም ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ መሎጊያዎችን ፡ ሠርተህ ፡ በናስ ፡ ለብጣቸው ። ፯ መሎጊያዎቹም ፡ በቀለበቶች ፡ ውስጥ ፡ ይግቡ ፤ መሠዊያውንም ፡ ስትሸከሙ ፡ መሎጊያዎቹ ፡ በሁለቱ ፡ ወገኖች ፡ ይሁኑ ። ፰ ከሳንቆች ፡ ሠርተህ ፡

በዶ ፡ አድርገው ፤ በተራራው ፡ እንዳስየሁህ ፡
ምሳሌ ፡ እንዲሁ ፡ ያድርጉት ።

፱ የማደሪያውንም ፡ አደባባይ ፡ ሥራ ፤ በደቡብ ፡
ወገን ፡ የጥሩ ፡ በፍታ ፡ መጋረጆች ፡ ይሁኑለት ፥
የአንዱም ፡ ወገን ፡ ርዝመት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ ይሁን ፤
፲ ከናስ ፡ የተሠሩ ፡ ሀያ ፡ ምሰሶችና ፡ ሀያ ፡ እግሮች ፡
ይሁኑለት ፤ የምሰሶቹም ፡ ኩላቦችና ፡ ዘንጎች ፡
፲፩ የብር ፡ ይሁኑ ። እንዲሁም ፡ በሰሜን ፡ ወገን ፡
መቶ ፡ ክንድ ፡ ርዝመት ፡ ያላቸው ፡ መጋረጆች ፥
ከናስ ፡ የተሠሩ ፡ ሀያ ፡ ምሰሶች ፡ ሀያም ፡ እግሮች ፡
ይሁኑ ፤ ስምሰሶችም ፡ የብር ፡ ኩላቦችና ፡ ዘን
፲፪ ጎች ፡ ይሁኑ ። በምዕራብም ፡ ወገን ፡ ለአደባባዩ ፡
ስፋት ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ርዝመት ፡ ያላቸው ፡
መጋረጆች ፥ አሥርም ፡ ምሰሶች ፥ አሥርም ፡
፲፫ እግሮች ፡ ይሁኑለት ። በምሥራቅም ፡ ወገን ፡
፲፬ የአደባባዩ ፡ ስፋት ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ይሁን ። በአ
ንድ ፡ ወገን ፡ የመጋረጆቹ ፡ ርዝመት ፡ አሥራ ፡
አምስት ፡ ክንድ ፡ ይሁን ፤ ምሰሶቹም ፡ ሦስት ፥
፲፭ እግሮቹም ፡ ሦስት ፡ ይሁኑ ። በሌላውም ፡ ወገን ፡
የመጋረጆች ፡ ርዝመት ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡
ክንድ ፡ ይሆናል ፤ ምሰሶቹም ፡ ሦስት ፥ እግሮ
፲፮ ቹም ፡ ሦስት ፡ ይሁኑ ። ለአደባባዩም ፡ ደጅ ፡
ከሰማያዊ ፡ ከሐምራዊም ፡ ከቀይም ፡ ግምጃ ፡
ከጥሩ ፡ በፍታም ፡ በጥልፍ ፡ አሠራር ፡ የተሠራ ፡
ሀያ ፡ ክንድ ፡ መጋረጃ ፡ ይሆናል ፤ ምሰሶቹም ፡
፲፯ አራት ፥ እግሮቹም ፡ አራት ፡ ይሁኑ ። በአደባ
ባዩም ፡ ዙሪያ ፡ ላሉቱ ፡ ምሰሶች ፡ ሁሉ ፡ የብር ፡
ዘንጎች ፥ የብርም ፡ ኩላቦች ፥ የናስም ፡ እግ
፲፰ ሮች ፡ ይሁኑላቸው ። የአደባባዩ ፡ ርዝመት ፡
መቶ ፡ ክንድ ፡ ስፋቱም ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ይሁን ፥
የመጋረጃውም ፡ ከፍታ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡
ይሁን ፤ መጋረጃውም ፡ ከጥሩ ፡ በፍታ ፥ እግሮ
፲፱ ቹም ፡ ከናስ ፡ የተሠሩ ፡ ይሁኑ ። ለማገልገል ፡
ሁሉ ፡ የማደሪያው ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፥ ካስማዎቹም ፡
ሁሉ ፡ የአደባባዩም ፡ ካስማዎች ፡ ሁሉ ፥ የናስ ፡
ይሁኑ ።

፳ አንተም ፡ መብራቱን ፡ ሁልጊዜ ፡ ያበሩት ፡
ዘንድ ፡ ስመብራት ፡ ተወቅጦ ፡ የተጠለለ ፡ ጥሩ ፡
የወይራ ፡ ዘይት ፡ እንዲያመጡልህ ፡ የእስራኤ
፳፩ ልን ፡ ልጆች ፡ እዘዛቸው ። በመገናኛው ፡ ድን
ኳን ፡ ውስጥ ፡ በምስክሩ ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ ባለው ፡
መጋረጃ ፡ ውጭ ፡ አሮንና ፡ ልጆቹ ፡ ከማታ ፡
እስከ ፡ ማለዳ ፡ ድረስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
እንዲበራ ፡ ያሰናዱት ፤ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ዘንድ ፡ ለልጅ ፡ ልጃቸው ፡ የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡
ይሁን ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

፩ አንተም ፡ ወንድምህን ፡ አሮንን ፡ ከእርሱም ፡
ጋር ፡ ልጆቹን ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡
ለይተህ ፡ ካህናት ፡ ይሆኑልኝ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡
አቅርብ ፤ አሮንን ፡ የአሮንንም ፡ ልጆች ፥ ናዳ
ብን ፡ አብዩድንም ፡ አልዓዛርንም ፡ ኢታምር
፪ ንም ፥ አቅርብ ። የተቀደሰውንም ፡ ልብስ ፡ ለክብ
ርና ፡ ለጌጥ ፡ እንዲሆን ፡ ለወንድምህ ፡ ለአሮን ፡
፫ ሥራለት ። አንተም ፡ ካህን ፡ ሆኖ ፡ እንዲያገለግ
ለኝ ፡ አሮን ፡ ቅዱስ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ልብስ ፡ እንዲ
ሠሩለት ፡ የጥበብ ፡ መንፈስ ፡ ለሞላሁባቸው ፡ በል
ባቸው ፡ ጥበበኞች ፡ ለሆኑት ፡ ሁሉ ፡ ተናገር ።
፬ የሚሠሩአቸውም ፡ ልብሶች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤
የደረት ፡ ኪስ ፡ ኤፉድም ፡ ቀሚስም ፡ ዝንጕር
ጕር ፡ ሸሚዝም ፡ መጠምጠሚያም ፡ መታጠቂ
ያም ፤ እነዚህም ፡ ካህናት ፡ ይሆኑልኝ ፡ ዘንድ ፡
ለወንድምህ ፡ ለአሮን ፡ ለልጆቹም ፡ የተቀደሰ ፡
፭ ልብስ ፡ ያድርጉ ። ወርቅንም ፥ ሰማያዊና ፡ ሐም
ራዊ ፡ ቀይም ፡ ግምጃ ፥ ጥሩ ፡ በፍታም ፡ ይው
ሰዱ ።

፮ ኤፉዱንም ፡ በብልሃት ፡ የተሠራ ፡ በወርቅና ፡
በሰማያዊ ፡ በሐምራዊም ፡ በቀይም ፡ ግምጃ ፡
ከተፈተለ ፡ ከጥሩ ፡ በፍታም ፡ ብልሀ ፡ ሠራተኛ ፡
፯ እንደሚሠራ ፡ ያድርጉ ። ሁለቱ ፡ ወገን ፡ አንድ ፡
እንዲሆን ፡ በሁለቱ ፡ ጫንቃ ፡ ላይ ፡ የሚጋጠም ፡
፰ ጨርቅ ፡ ይሁን ። በላዩም ፡ መታጠቂያ ፡ ሆኖ ፡
በብልሃት ፡ የተጠለፈው ፡ የኤፉድ ፡ ቋድ ፡ እንደ ፡
እርሱ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ይሁን ፤ ከወር
ቅና ፡ ከሰማያዊ ፡ ከሐምራዊ ፡ ከቀይ ፡ ግምጃም ፡
ከተፈተለ ፡ ከጥሩ ፡ በፍታም ፡ የተሠራ ፡ ይሁን ።
፱ ሁለትም ፡ የመረግድ ፡ ድንጋይ ፡ ወስደህ ፡ የእ
ስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ስም ፡ ስማቸውን ፡ ቅረጽባ
፲ ቸው ፤ እንደ ፡ አወላለዳቸው ፡ ስድስት ፡ ስም ፡
በአንድ ፡ ድንጋይ ፥ የቀረውንም ፡ ስድስቱን ፡
፲፩ ስም ፡ በሌላው ፡ ቅረጽ ። በቅርጽ ፡ ሠራተኛ ፡
ሥራ ፡ እንደ ፡ ማኅተም ፡ ቅርጽ ፡ አድርገህ ፡ የእ
ስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ስም ፡ በሁለት ፡ ድንጋዮች ፡
፲፪ ቅረጽ ፤ በወርቅም ፡ ፈርጥ ፡ አድርግ ። የእስራ
ኤል ፡ ልጆችም ፡ የመታሰቢያ ፡ ድንጋዮች ፡
ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ሁለቱን ፡ ዕንቍዎች ፡ በኤፉዱ ፡
ጫንቃዎች ፡ ላይ ፡ ታደርጋለህ ፤ አሮንም ፡
በሁለቱ ፡ ጫንቃዎች ፡ ላይ ፡ ለመታሰቢያ ፡ ስማ
ቸውን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይሸከማል ።
፲፫፡፲፬ የወርቅም ፡ ፈርጦች ፡ ሁለትም ፡ ድሪዎች ፡ ከጥሩ ፡
ወርቅ ፡ ሥራ ፤ እንደ ፡ ትጕንጕንም ፡ ገመድ ፡ አድ
ርግ ፤ የተጕነጐኑትንም ፡ ድሪዎች ፡ በፈርጦቹ ፡
ላይ ፡ አንጠልጥል ።

፲፭ ብልሀ ፡ ሠራተኛም ፡ እንደሚሠራ ፡ የፍር
ዱን ፡ የደረት ፡ ኪስ ፡ ሥራው ፤ እንደ ፡ ኤፉ
ዱም ፡ አሠራር ፡ ሥራው ፤ ከወርቅና ፡ ከሰማያዊ ፡
ከሐምራዊም ፡ ከቀይም ፡ ግምጃ ፡ ከጥሩ ፡ በፍ
፲፮ ታም ፡ ሥራው ። ርዝመቱ ፡ ስንዝር ፡ ስፋቱም ፡
ስንዝር ፡ ሆኖ ፡ ትክክልና ፡ ድርብ ፡ ይሆናል ።
፲፯ በአራት ፡ ተራ ፡ የሆነ ፡ የዕንቍ ፡ ፈርጥ ፡ አድር
ግበት ፤ በፊተኛው ፡ ተራ ፡ ሰርድዮን ፥ ቶጳዝ
፲፰ ዮን ፥ የሚያብረቀርቅ ፡ ዕንቍ ፤ በሁለተኛውም ፡
፲፱ ተራ ፡ በሉር ፥ ሰንፔር ፥ አልማዝ ፤ በሦስተኛ
ውም ፡ ተራ ፡ ያክንት ፥ ኬልቄዶን ፥ አሜቴ
፳ ስጢኖስ ፤ በአራተኛውም ፡ ተራ ፡ ቢረሌ ፥ መረ
ግድ ፥ ኢያስጲድ ፡ በወርቅ ፡ ፈርጥ ፡ ይደረ
፳፩ ጋሉ ። የዕንቍቹም ፡ ድንጋዮች ፡ እንደ ፡ እስራ

ኤል ፡ ልጆች ፡ ስሞች ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ይሆናሉ ፤ በየስማቸውም ፡ ማተሚያ ፡ እንደሚቀረጽ ፡ ይቀረጹ ፤ ስለ ፡ አሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ነገዶችም ፡ ይሁኑ ። ለደረቱ ፡ ኪስም ፡ የተጐነጐኑትን ፡ ድሪዎች ፡ እንደ ፡ ገመድ ፡ አድርገህ ፡ ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ሥራቸው ። ለደረቱ ፡ ኪስም ፡ ሁለት ፡ የወርቅ ፡ ቀለበቶች ፡ ሥራ ፥ ሁለቱንም ፡ ቀለበቶች ፡ በደረቱ ፡ ኪስ ፡ በሁለቱ ፡ ወገን ፡ አድርጋቸው ። የተጐነጐኑትንም ፡ ሁለቱን ፡ የወርቅ ፡ ድሪዎች ፡ በደረቱ ፡ ኪስ ፡ ወገኖች ፡ ወዳሉት ፡ ወደ ፡ ሁለቱ ፡ ቀለበቶች ፡ ታገባቸዋለህ ። የሁለቱንም ፡ ድሪዎች ፡ ጫፎች ፡ በሁለቱ ፡ ፈርጦች ፡ ውስጥ ፡ አግብተህ ፡ በኤፉዱ ፡ ጫንቃዎች ፡ ላይ ፡ በፊታቸው ፡ ታደርጋቸዋለህ ። ሁለት ፡ የወርቅ ፡ ቀለበቶችም ፡ ሥራ ፥ እነርሱንም ፡ በኤፉዱ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ባለው ፡ በደረቱ ፡ ኪስ ፡ በሁለቱ ፡ ጫፎች ፡ ላይ ፡ ታደርጋቸዋለህ ። ደግሞም ፡ ሁለት ፡ የወርቅ ፡ ቀለበቶች ፡ ሥራ ፥ በኤፉዱም ፡ ፊት ፡ ከጫንቃዎች ፡ በታች ፡ በብልሃት ፡ ከተጠለፈ ፡ ከኤፉዱ ፡ ቋድ ፡ በላይ ፡ በመያዣው ፡ አጠገብ ፡ ታደርጋቸዋለህ ። የደረቱም ፡ ኪስ ፡ በብልሃት ፡ ከተጠለፈ ፡ ከኤፉዱ ፡ ቋድ ፡ በላይ ፡ እንዲሆን ፡ ከኤፉዱም ፡ እንዳይለይ ፥ የደረቱን ፡ ኪስ ፡ ከቀለበቶቹ ፡ ወደ ፡ ኤፉዱ ፡ ቀለበቶች ፡ በሰማያዊ ፡ ፈትል ፡ ያስሩታል ። አሮንም ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለዘላለም ፡ መታሰቢያ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ስሞች ፡ በፍርዱ ፡ በደረት ፡ ኪስ ፡ ውስጥ ፡ በልቡ ፡ ላይ ፡ ይሸከም ። በፍርዱ ፡ በደረት ፡ ኪስም ፡ ውስጥ ፡ ኡሪምንና ፡ ቱሚምን ፡ ታደርጋለህ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ በአሮን ፡ ልብ ፡ ላይ ፡ ይሆናሉ ፤ አሮንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሁልጊዜ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ፍርድ ፡ በልቡ ፡ ላይ ፡ ይሸከማል ።

የኤፉዱንም ፡ ቀሚስ ፡ ሁሉ ፡ ሰማያዊ ፡ አድርገው ። ከላይም ፡ በመካከል ፡ አንገትጌ ፡ ይሁንበት ፤ እንዳይቀደድም ፡ እንደ ፡ ጥሩር ፡ የተሠራ ፡ ጥልፍ ፡ በአንገትጌው ፡ ዙሪያ ፡ ይሁንበት ። በታችኛውም ፡ ዘርፍ ፡ ዙሪያ ፡ ከሰማያዊ ፡ ከሐምራዊም ፡ ከቀይም ፡ ግምጃ ፡ ሮማኖች ፡ አድርግ ፤ በዚያም ፡ መካከል ፡ በዙሪያው ፡ የወርቅ ፡ ሻኩራዎች ፡ አድርግ ፤ የወርቅ ፡ ሻኩራ ፡ ሮማንም ፥ ሌላም ፡ የወርቅ ፡ ሻኩራ ፡ ሮማንም ፡ በቀሚሱ ፡ ዘርፍ ፡ ዙሪያውን ፡ ይሆናሉ ። በማገልገል ፡ ጊዜም ፡ በአሮን ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፤ እርሱም ፡ እንዳይሞት ፡ ወደ ፡ መቅደሱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሲገባና ፡ ሲወጣ ፡ ድምፁ ፡ ይሰማል ።

ከጥሩ ፡ ወርቅም ፡ ቅጠል ፡ የሚመስል ፡ ምልክት ፡ ሥራ ፥ በእርሱም ፤ እንደ ፡ ማኅተም ፡ ቅርጽ ፡ አድርገህ — ቅድስና ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚል ፡ ትቀርጽበታለህ ። በሰማያዊም ፡ ፈትል ፡ በመጠምጠሚያው ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ ታንጠለጥለዋለህ ። በአሮንም ፡ ግምባር ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፥ አሮንም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በሚያቀርቡትና ፡ በሚቀድሱት ፡ በቅዱስ ፡ ስጦታቸው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ኃጢአት ፡ ይሸከም ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ሞገስ ፡ እንዲሆንላቸው ፡ ቅጠል ፡ የሚመስለው ፡ ምልክቱ ፡ ሁልጊዜ ፡ በግምባሩ ፡ ላይ ፡ ይሁን ። ፴፱ ሸሚዙንም ፡ ከጥሩ ፡ በፍታ ፡ ዝንጕርጕር ፡ አድርገህ ፥ መጠምጠሚያውን ፡ ከበፍታ ፡ ትሠራለህ ፤ በጥልፍ ፡ አሠራር ፡ መታጠቂያም ፡ ትሠራለህ ።

፵ ለአሮንም ፡ ልጆች ፡ ሸሚዞችን ፡ መታጠቂያዎችንም ፡ ቆቦችንም ፡ ለክብርና ፡ ለጌጥ ፡ ታደርግላቸዋለህ ። ፵፩ ይህንም ፡ ሁሉ ፡ ወንድምህን ፡ አሮንን ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ልጆቹን ፡ ታለብሳቸዋለህ ፤ በክህነት ፡ እንዲያገለግሉኝ ፡ ትቀባቸዋለህ ፥ ትክናቸዋለህ ፥ ትቀድሳቸውማለህ ። ፵፪ ኀፍረተ ፡ ሥጋቸውንም ፡ ይከድኑበት ፡ ዘንድ ፡ የበፍታ ፡ ሱሪ ፡ ታደርግላቸዋለህ ፤ ከወገባቸውም ፡ እስከ ፡ ጭናቸው ፡ ይደርሳል ፤ ፵፫ ኃጢአትም ፡ እንዳይሆንባቸው ፡ እንዳይሞቱም ፥ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ሲገቡ ፡ በመቅደሱም ፡ ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መሠዊያው ፡ ሲቀርቡ ፡ በአሮንና ፡ በልጆቹ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፤ ለእርሱ ፡ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ለዘሩ ፡ ለዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ይሆናል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

፩ እኔንም ፡ በክህነት ፡ እንዲያገለግሉኝ ፡ ትቀድሳቸው ፡ ዘንድ ፡ የምታደርግባቸው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ነውር ፡ የሌለባቸውን ፡ አንድ ፡ ወይፈንና ፡ ሁለት ፡ አውራ ፡ በጎች ፡ ትወስዳለህ ። ፪ ቂጣ ፡ እንጀራ ፥ በዘይትም ፡ የተለወሰ ፡ የቂጣ ፡ እንጐቻ ፥ በዘይትም ፡ የተቀባ ፡ ስስ ፡ ቂጣ ፡ ከመልካም ፡ ስንዴ ፡ ታደርጋለህ ። ፫ በአንድ ፡ ሌማትም ፡ ታደርጋቸዋለህ ፤ ከወይፈኑና ፡ ከሁለቱ ፡ አውራ ፡ በጎች ፡ ጋር ፡ በሌማቱ ፡ ታቀርባቸዋለህ ። ፬ አሮንንና ፡ ልጆቹንም ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ታቀርባቸዋለህ ፥ በውኃም ፡ ታጥባቸዋለህ ። ፭ ልብሶችን ፡ ወስደህ ፡ ለአሮን ፡ ሸሚዝና ፡ የኤፉድ ፡ ቀሚስ ፡ ኤፉድም ፡ የደረት ፡ ኪስም ፡ ታለብሰዋለህ ፥ በብልሃትም ፡ በተጠለፈ ፡ ቋድ ፡ ታስታጥቀዋለህ ፤ ፮ መጠምጠሚያውንም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ታደርጋለህ ፥ የተቀደሰውንም ፡ አክሊል ፡ በመጠምጠሚያው ፡ ላይ ፡ ታኖራለህ ። ፯ የቅብዓቱንም ፡ ዘይት ፡ ወስደህ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ታፈስሰዋለህ ፥ ትቀባውማለህ ። ፰ ልጆቹንም ፡ ታቀርባቸዋለህ ፥ ሸሚዞቹንም ፡ ታለብሳቸዋለህ ። ፱ አሮንንና ፡ ልጆቹንም ፡ በመታጠቂያ ፡ ታስታጥቃቸዋለህ ፥ ቆብንም ፡ ታለብሳቸዋለህ ፤ ለዘላለም ፡ ሥርዓትም ፡ ክህነት ፡ ይሆንላቸዋል ፤ እንዲሁም ፡ አሮንንና ፡ ልጆቹን ፡ ትክናቸዋለህ ።

፲ ወይፈኑንም ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ በር ፡ ፊት ፡ ታቀርበዋለህ ፤ አሮንና ፡ ልጆቹም ፡ እጃቸውን ፡ በወይፈኑ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይጭናሉ ። ፲፩ ወይፈኑንም ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ በር ፡

አጠገብ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ታርደዋለህ ።
፲፪ ከወይፈኑም ፡ ደም ፡ ወስደህ ፡ በመሠዊያው ፡ ቀንዶች ፡ ላይ ፡ በጣትህ ፡ ትረጨዋለህ ፤ ደሙንም ፡ ሁሉ ፡ ከመሠዊያው ፡ በታች ፡ ታፈስሰዋለህ ።
፲፫ የሆድ ፡ ዕቃውንም ፡ የሚሸፍነውን ፡ ስብ ፡ ሁሉ ፡ በጉበቱም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ መረብ ፡ ሁለቱንም ፡ ኵላሊቶች ፡ በላያቸውም ፡ ያለውን ፡ ስብ ፡ ወስደህ ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ታቃጥላለህ ።
፲፬ የወይፈኑን ፡ ሥጋ ፡ ግን ፥ ቍርበቱንም ፥ ፈርሱንም ፡ ከሰፈር ፡ ውጭ ፡ በእሳት ፡ ታቃጥለዋለህ ፤ የኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ነው ።
፲፭ አንደኛውንም ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ትወስደዋለህ ፤ አሮንና ፡ ልጆቹም ፡ በአውራው ፡ በግ ፡ ራስ ፡
፲፮ ላይ ፡ እጆቻቸውን ፡ ይጭናሉ ። አውራውንም ፡ በግ ፡ ታርደዋለህ ፥ ደሙንም ፡ ወስደህ ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ በዙሪያው ፡ ትረጨዋለህ ።
፲፯ አውራውንም ፡ በግ ፡ በየብልቱ ፡ ትቈርጠዋለህ ፥ የሆድ ፡ ዕቃውንና ፡ እግሮቹንም ፡ ታጥበህ ፥ ከብልቱና ፡ ከራሱም ፡ ጋር ፡ ታኖረዋለህ ።
፲፰ አውራውንም ፡ በግ ፡ በሙላው ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ታቃጥላለህ ፤ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ነው ፤ ጣፋጭ ፡ሽቱ ፡ ነው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የቀረበ ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ነው ።
፲፱ ሁለተኛውንም ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ትወስደዋለህ ፤ አሮንና ፡ ልጆቹም ፡ እጆቻቸውን ፡ በአ
፳ ውራው ፡ በግ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይጭናሉ ። አውራውንም ፡ በግ ፡ ታርደዋለህ ፥ ደሙንም ፡ ትወስዳለህ ፥ የአሮንንም ፡ የቀኝ ፡ ጆሮ ፡ ጫፍ ፥ የልጆቹንም ፡ የቀኝ ፡ ጆሮአቸውን ፡ ጫፍ ፥ የቀኝ ፡ እጃቸውንና ፡ የቀኝ ፡ እግራቸውን ፡ አውራ ፡ ጣት ፡ ታስነካለህ ፤ ደሙንም ፡ በመሠዊያው ፡
፳፩ ላይ ፡ በዙሪያው ፡ ትረጨዋለህ ። በመሠዊያውም ፡ ላይ ፡ ካለው ፡ ደም ፡ ከቅብዓት ፡ ዘይትም ፡ ወስደህ ፡ በአሮንና ፡ በልብሱ ፡ ላይ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ባሉት ፡ በልጆቹና ፡ በልብሶቻቸው ፡ ላይ ፡ ትረጨዋለህ ፤ እርሱም ፡ ልብሶቹም ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ልጆቹ ፡ ልብሶቻቸውም ፡ ይቀደ
፳፪ ሳሉ ። ደግሞም ፡ የሚክኑበት ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ነውና ፡ የበጉን ፡ ስብ ፥ ላቱንም ፥ የሆድ ፡ ዕቃውንም ፡ የሚሸፍነውን ፡ ስብ ፥ በጉበቱም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ መረብ ፥ ሁለቱንም ፡ ኵላሊቶች ፡ በላያቸውም ፡ ያለውን ፡ ስብ ፥ የቀኙንም ፡ ወርች ፡
፳፫ ትወስዳለህ ። አንድ ፡ እንጀራ ፥ አንድም ፡ የዘይት ፡ እንጀራ ፥ አንድም ፡ ስስ ፡ ቂጣ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በሌማት ፡ካለው ፡ ቂጣ ፡ እን
፳፬ ጀራ ፡ ትወስዳለህ ፤ ሁሉንም ፡ በአሮን ፡ እጆችና ፡ በልጆቹ ፡ እጆች ፡ ታኖረዋለህ ፤ ለሚወዘወዝ ፡ ቍርባን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
፳፭ ትወዘውዘዋለህ ። ከእጃቸውም ፡ ትቀበለዋለህ ፥ በመሠዊያውም ፡ ላይ ፡ ከሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ጋር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ጣፋጭ ፡ ሽቱ ፡ እንዲሆን ፡ ታቃጥለዋለህ ፤ እርሱ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ነው ።

፳፮ ለአሮንም ፡ ክህነት ፡ የታረደውን ፡ የአውራውን ፡ በግ ፡ ፍርምባ ፡ ወስደህ ፡ ለሚወዘወዝ ፡ ቍርባን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ትወዘውዘዋለህ ፤ እርሱም ፡ የአንተ ፡ ወግ ፡ ይሆናል ።
፳፯ ከሚክኑበትም ፡ አውራ ፡ በግ ፡ የተወሰደ ፡ ለአሮንና ፡ ለልጆቹ ፡ ወግ ፡ የሚሆን ፡ ለመሥዋዕት ፡ የተወዘወዘውን ፡ ፍርምባና ፡ የተነሣውን ፡ ወርች ፡
፳፰ ትቀድሳለህ ። ያውም ፡ የማንሣት ፡ ቍርባን ፡ ነውና ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ ለዘላለም ፡ የአሮንና ፡ የልጆቹ ፡ ወግ ፡ ይሁን ፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የሚያቀርቡት ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋዕታቸው ፡ የማንሣት ፡ ቍርባን ፡ ይሆናል ፤ ለእግዚአብሔር ፡ የማንሣት ፡ ቍርባን ፡ ይሆናል ።
፳፱ የተቀደሰውም ፡ የአሮን ፡ ልብስ ፡ ይቀቡበትና ፡ ይክኑበት ፡ ዘንድ ፡ ከእርሱ ፡ በኋላ ፡ ለልጆቹ ፡ ይሁን ።
፴ ከልጆቹም ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ካህን ፡ የሚሆነው ፡ በመቅደስ ፡ ለማገልገል ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ሲገባ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ይልበሰው ።
፴፩ የሚክንበትንም ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ወስደህ ፡ ሥጋውን ፡ በተቀደሰ ፡ስፍራ ፡ ትቀቅለዋለህ ።
፴፪ አሮንና ፡ ልጆቹም ፡ የአውራውን ፡ በግ ፡ ሥጋ ፡ በሌማትም ፡ ያለውን ፡ እንጀራ ፡ በመገናኛው ፡
፴፫ ድንኳን ፡ በር ፡ ይበሉታል ። የተካኑና ፡ የተቀደሱ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ማስተስረያ ፡ የሆነውን ፡ ነገር ፡ ይብሉት ፤ ሌላ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ አይብላው ፤
፴፬ የተቀደሰ ፡ ነውና ። የተካኑበትም ፡ ሥጋ ፡ ወይም ፡ እንጀራ ፡ ተርፎ ፡ ቢያድር ፥ የቀረውን ፡ በእሳት ፡ ታቃጥለዋለህ ፤ የተቀደሰ ፡ ነውና ፡ አይበላም ።
፴፭ እንዳዘዝሁህም ፡ ሁሉ ፡ በአሮንና ፡ በልጆቹ ፡ እንዲህ ፡ አድርግ ፤ ሰባት ፡ ቀን ፡ ትክናቸዋለህ ።
፴፮ ዕለት ፡ ዕለትም ፡ ስለ ፡ማስተስረይ ፡ ስኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ወይፈኑን ፡ ታቀርባለህ ፤ ማስተስረያም ፡ በደረግህ ፡ ጊዜ ፡ መሠዊያውን ፡ ታነጻዋለህ ፤ ቅዱስም ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ትቀባዋለህ ።
፴፯ ሰባት ፡ ቀን ፡ ለመሠዊያው ፡ ማስተስረያ ፡ ታደርጋለህ ፥ ትቀድሰውማለህ ፤ መሠዊያውም ፡ ቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፡ ይሆናል ፤ መሠዊያውንም ፡ የሚነካ ፡ ሁሉ ፡ ቅዱስ ፡ ይሆናል ።
፴፰ በመሠዊያውም ፡ ላይ ፡ የምታቀርበው ፡ ይህ ፡ ነው ፤ በቀን ፡ በቀን ፡ ዘወትር ፡ ሁለት ፡ የዓመት ፡
፴፱ ጠቦቶች ፡ ታቀርባለህ ። አንዱን ፡ ጠቦት ፡ በማለዳ ፡ ቍርባን ፡ አድርገህ ፡ ታቀርበዋለህ ፤ ሁለተኛውንም ፡ ጠቦት ፡ በማታ ፡ ቍርባን ፡ አድርገህ ፡
፵ ታቀርበዋለህ ። ከአንዱ ፡ ጠቦትም ፡ ጋር ፡ የኢን ፡ መስፈሪያ ፡ አራተኛ ፡ እጅ ፡ በሆነ ፡ ተወቅጦ ፡ በተጠለለ ፡ ዘይት ፡ የተለወሰ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ አሥረኛ ፡ እጅ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፥ ደግሞ ፡ ለመጠጥ ፡ ቍርባን ፡ የኢን ፡ መስፈሪያ ፡ አራተኛ ፡ እጅ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ታቀርባለህ ።
፵፩ ሁለተኛውንም ፡ ጠቦት ፡ በማታ ፡ ታቀርበዋለህ ፥ እንደ ፡ ማለዳውም ፡ የእህልና ፡ የመጠጥ ፡ ቍርባን ፡ ታደርግበታለህ ፤ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡

ሽቱ ፡ እንዲሆን ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ይሆናል ። ፵፪ ለአንተ ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ በምገናኝበት ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፥ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይህ ፡ ዘወትር ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ይሆናል ። ፵፫ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ በዚያ ፡ እገናኛለሁ ፤ ፵፬ ድንኳኑም ፡ በክብሬ ፡ ይቀደሳል ። የመገናኛውንም ፡ ድንኳን ፡ መሠዊያውንም ፡ እቀድሳለሁ ፤ በክህነትም ፡ ያገለግሉኝ ፡ ዘንድ ፡ አሮንንና ፡ ልጆቹን ፡ እቀድሳለሁ ። ፵፭ በእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ እኖራለሁ ፥ አምላክም ፡ እሆናቸዋለሁ ። ፵፮ በመካከላቸውም ፡ እኖር ፡ ዘንድ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣኋቸው ፡ አምላካቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ እኔ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ፤ እኔ ፡ አምላካቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

፩ የዕጣን ፡ መሠዊያውን ፡ ሥራ ፤ ከግራር ፡ እንጨት ፡ አድርገው ። ፪ ርዝመቱ ፡ አንድ ፡ ክንድ ፥ ስፋቱም ፡ አንድ ፡ ክንድ ፥ አራት ፡ ማዕዘን ፡ ይሁን ፤ ከፍታውም ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፡ ይሆናል ፤ ቀንዶቹም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በአንድነት ፡ የተሠሩ ፡ ይሁኑ ። ፫ ላይኛውንና ፡ የግድግዳውንም ፡ ዙሪያ ፡ ቀንዶቹንም ፡ በጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ትለብጠዋለህ ፤ በዙሪያውም ፡ የወርቅ ፡ ክፈፍ ፡ታደርግለታለህ ። ፬ ከክፈፉም ፡ በታች ፡ ሁለት ፡ የወርቅ ፡ ቀለበቶች ፡ አድርግለት ። በዚህና ፡ በዚያ ፡ በሁለቱ ፡ ጎን ፡ ታደርጋቸዋለህ ፤ ለመሸከምም ፡ የመሎጊያዎች ፡ ስፍራ ፡ ይሁኑ ። ፭ መሎጊያዎቹንም ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ አድርግ ፥ በወርቅም ፡ ለብጣቸው ። ፮ በምስክሩ ፡ ታቦት ፡ አጠገብም ፡ ካለው ፡ መጋረጃ ፡ በፊት ፡ ታኖረዋለህ ፡ ይህንም ፡ አንተን ፡ በምገናኝበት ፡ ከምስክሩ ፡ በላይ ፡ ባለው ፡ በስርየት ፡ መክደኛ ፡ ፊት ፡ ታኖረዋለህ ። ፯ አሮንም ፡ የጣፋጭ ፡ ሽቱ ፡ ዕጣን ፡ ይጠንበት ፤ በማለዳ ፡ በማለዳ ፡ መብራቶቹን ፡ ሲያዘጋጅ ፡ ይጠነው ። ፰ ይህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ የዘወትር ፡ ዕጣን ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ አሮን ፡ በማታ ፡ ጊዜ ፡ መብራቶቹን ፡ ሲያበራ ፡ ያጥነዋል ። ፱ ሌላም ፡ ዕጣን ፥ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፥ የእህሉንም ፡ ቍርባን ፡ አታቀርብበትም ፤ የመጠጥም ፡ ቍርባን ፡ አታፈስስበትም ። ፲ አሮንም ፡ በዓመት ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ በቀንዶቹ ፡ ላይ ፡ ማስተስረያ ፡ ያደርጋል ፤ በዓመት ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ ማስተስረያ ፡ በሚሆን ፡ በኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ደም ፡ ማስተስረያ ፡ ያደርግበታል ። ለእግዚአብሔር ፡ ቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፡ ናት ።

፲፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፦ ፲፪ አንተ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ቍጥር ፡ ተቀብለህ ፥ በቈጠርሃቸው ፡ ጊዜ ፡ መቅሠፍት ፡ እንዳይሆንባቸው ፥ በቈጠርሃቸው ፡ ጊዜ ፡ ከእነርሱ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ቍጥራቸው ፡ መጠን ፡ የነፍሱን ፡ ቤዛ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይስጥ ። ፲፫ አልፎ ፡ የሚቈጠር ፡ ሁሉ ፡ ግማሽ ፡ ሰቅል ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፤ ሚዛን ፡ ይሰጣል ፤ የሰቅል ፡ ግማሽ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያነሣል ። ሰቅሉ ፡ ሀያ ፡ አቦሊ ፡ ነው ። ፲፬ አልፎ ፡ የተቈጠረ ፡ ሁሉ ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ ከፍ ፡ ያለ ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ስጦታ ፡ ይሰጣል ። ፲፭ ለነፍሳችሁ ፡ ማስተስረያ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስጦታ ፡ ስትሰጡ ፡ ባለ ፡ ጠጋው ፡ ከሰቅል ፡ ግማሽ ፡ አይጨምር ፥ ድሀውም ፡ አያጕድል ። ፲፮ የማስተስረያውንም ፡ ገንዘብ ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወስደህ ፡ ለመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ማገልገያ ፡ ታደርገዋለህ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ለነፍሳችሁ ፡ ቤዛ ፡ እንዲሆን ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መታሰቢያ ፡ ይሁን ።

፲፯ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፦ ፲፰ የመታጠቢያ ፡ ሰንና ፡ መቀመጫውን ፡ ከናስ ፡ ሥራ ፤ በመገናኛው ፡ ድንኳንና ፡ በመሠዊያው ፡ መካከል ፡ አርሱን ፡ አድርገህ ፡ ውኃን ፡ ትጨምርበታለህ ። ፲፱ አሮንና ፡ ልጆቹም ፡ እጆቻቸውንና ፡ እግሮቻቸውን ፡ ይታጠቡበታል ። ፳ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፥ ለእግዚአብሔርም ፡ የእሳት ፡ መሥዋዕት ፡ ያቃጥሉ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መሠዊያው ፡ ሊያገለግሉ ፡ በቀረቡ ፡ ጊዜ ፥ እንዳይሞቱ ፡ ይታጠቡበታል ። ፳፩ እንዳይሞቱም ፡ እጆቻቸውንና ፡ እግሮቻቸውን ፡ ይታጠቡ ፤ ይህም ፡ ለእርሱ ፡ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ለዘሩ ፡ የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ይሆንላቸዋል ።

፳፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፦ ፳፫ አንተም ፡ ከቡሩን ፡ ሽቱ ፡ ውሰድ ፤ የተመረጠ ፡ ከርቤ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ሰቅል ፥ ግማሽም ፡ጣፋጭ ፡ ቀረፋ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ሰቅል ፥ የጠጅ ፡ ሣርም ፡ እንዲሁ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ሰቅል ፥ ፳፬ ብርጕድም ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ሰቅል ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፥ የወይራ ፡ ዘይትም ፡ አንድ ፡ የኢን ፡ መስፈሪያ ፡ ትወስዳለህ ። ፳፭ በቀማሚም ፡ ብልሃት ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፡ ቅመም ፥ የተቀደሰ ፡ የቅብዓት ፡ ዘይት ፡ ታደርገዋለህ ፤ የተቀደሰ ፡ የቅብዓት ፡ ዘይት ፡ ይሆናል ። ፳፮ የመገናኛውንም ፡ ድንኳን ፥ የምስክሩንም ፡ ታቦት ፥ ፳፯ ገበታውንም ፡ ዕቃውንም ፡ ሁሉ ፥ መቅረዙንም ፡ ዕቃውንም ፥ የዕጣን ፡ መሠዊያውንም ፥ ፳፰ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆነውን ፡ መሠዊያና ፡ ዕቃውንም ፡ ሁሉ ፥ የመታጠቢያውን ፡ ሰንና ፡ መቀመጫውንም ፡ ትቀባበታለህ ። ፳፱ ሁሉንም ፡ ትቀድሳቸዋለህ ፥ ቅድስተ ፡ ቅዱሳንም ፡ ይሆናሉ ፤ የሚነካቸውም ፡ ሁሉ ፡ ቅዱስ ፡ ይሆናል ። ፴ በክህነትም ፡ ያገለግሉኝ ፡ ዘንድ ፡ አሮንንና ፡ ልጆቹን ፡ ቀብቸው ፥ ቀድሳቸውም ። ፴፩ አንተም ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ተናገር ፦ ይህ ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ የተቀደሰ ፡ የቅብዓት ፡ ዘይት ፡ ይሁንልኝ ። ፴፪ በሰው ፡ ሥጋ ፡ ላይ ፡ አይፍሰስ ፤ እንደ ፡ እርሱም ፡ የተሠራ ፡ ሌላ ፡ ቅብዓት ፡ አታድርጉ ፤ ቅዱስ ፡ ነው ፥ ለእናንተም ፡ ቅዱስ ፡

፴፫ ይሁን ። እንደ ፡ እርሱ ፡ ያለውን ፡ የሚያደርግ ፡ ሰው ፥ በሌላም ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ የሚያፈሰሰው ፡ ከሕዝቡ ፡ ተለይቶ ፡ ይጥፋ ።

፴፬ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— ጣፋጭ ፡ ሽቱ ፡ ውሰድ ፤ የሚንጠባጠብ ፡ ሙጫ ፥ በዛጎል ፡ ውስጥ ፡ የሚገኝ ፡ ሽቱ ፥ የሚሸትትም ፡ ሙጫ ፥ ጥሩም ፡ ዕጣን ፡ ውሰድ ፤ የሁሉም ፡ ፴፭ መጠን ፡ ትክክል ፡ ይሁን ። በቀማሚ ፡ ብልሃት ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፥ በጨው ፡ የተቀመመ ፡ ፴፮ ንጹሕና ፡ ቅዱስ ፡ ዕጣን ፡ አድርገው ። ከእርሱም ፡ ጥቂት ፡ ትወቅጣለህ ፥ ታልመውማለህ ፤ ከዚያም ፡ ወስደህ ፡ እንተን ፡ በምገናኝበት ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ በምስክሩ ፡ ፊት ፡ ታኖረዋለህ ። እርሱም ፡ የቅዱሳን ፡ ቅዱስ ፡ ፴፯ ይሁንላችሁ ። እንደ ፡ እርሱ ፡ የተሠራ ፡ ዕጣን ፡ ለእናንተ ፡ አታድርጉ ፤ በእናንተ ፡ ዘንድም ፡ ፴፰ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ ፡ ይሁን ። ሊያሸትተውም ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ የሚያደርግ ፡ ሰው ፡ ከሕዝቡ ፡ ተለይቶ ፡ ይጥፋ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፩ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፪ ተናገረው ፡— እይ ፡ ከይሁዳ ፡ ነገድ ፡ የሚሆን ፡ የሆር ፡ የልጅ ፡ ልጅ ፥ የኡሪ ፡ ልጅ ፡ በስልኤልን ፡ ፫ በስሙ ፡ ጠርቼዋለሁ ። በሥራ ፡ ሁሉ ፡ ብልሃት ፡ በጥበብም ፡ በማስተዋልም ፡ በእውቀትም ፡ ፬ የእግዚአብሔርን ፡ መንፈስ ፡ ሞላሁበት ፤ የጥበብን ፡ ሥራ ፡ ያስተውል ፡ ዘንድ ፥ በወርቅና ፡ ፭ በብር ፡ በናስም ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፥ ለፈርጥ ፡ የሚሆነውን ፡ የዕንቍ ፡ ድንጋይ ፡ ይቀርጽ ፡ ዘንድ ፥ እንጨቱንም ፡ ይጠርብ ፡ ዘንድ ፥ ሥራውንም ፡ ሁሉ ፡ ፮ ይሠራ ፡ ዘንድ ። እኔም ፡ እነሆ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ከዳን ፡ ነገድ ፡ የሚሆን ፡ የአሂሳሚክን ፡ ልጅ ፡ ኤልያብን ፡ ሰጠሁ ፤ ያዘዝሁህን ፡ ሁሉ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ በልባቸው ፡ ጥበበኞች ፡ በሆኑት ፡ ሁሉ ፡ ፯ ጥበብን ፡ አኖርሁ ። የመገናኛውን ፡ ድንኳን ፥ የምስክሩንም ፡ ታቦት ፥ በእርሱም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ የስርየት ፡ መክደኛውን ፥ የድንኳኑንም ፡ ፰ ዕቃ ፡ ሁሉ ፥ ገበታውንም ፡ ዕቃውንም ፥ ከዕቃው ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ የነጻውን ፡ መቅረዝ ፥ የዕ ፱ ጣን ፡ መሠዊያውን ፥ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆነውንም ፡ መሠዊያ ፡ ዕቃውንም ፡ ሁሉ ፥ የመታጠቢያውን ፡ ሰንም ፡ መቀመጫውንም ፥ ፲ በብልሃት ፡ የተሠራውንም ፡ ልብስ ፥ በክህነት ፡ እኔን ፡ የሚያገለግሉበትን ፡ የካህኑን ፡ የአሮንን ፡ ፲፩ ልብስ ፡ ተክህኖና ፡ የልጆቹን ፡ ልብስ ፥ የቅብዓቱንም ፡ ዘይት ፥ ለመቀደሱ ፡ የሚሆን ፡ የጣፋጭ ፡ ሽቱውንም ፡ ዕጣን ፡ እንዳዘዝሁህ ፡ ሁሉ ፡ ያድርጉ ።

፲፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ፲፫ ተናገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— እኔ ፡ የምቀድሳችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ በእኔና ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ ምልክት ፡ ነውና ፡ ሰንበቶቼን ፡ ፈጽሞ ፡ ጠብቁ ።

፲፬ ስለዚህ ፡ ለእናንተ ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ፡ ሰንበትን ፡ ጠብቁ ፤ የሚያረክሰውም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደል ፥ ሥራንም ፡ በእርሱ ፡ የሠራ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከሕዝቡ ፡ መካከል ፡ ተለይቶ ፡ ይጥፋ ። ፲፭ ስድስት ፡ ቀን ፡ ሥራን ፡ ሥራ ፤ ሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ግን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ ፡ የዕረፍት ፡ ሰንበት ፡ ነው ፤ በሰንበት ፡ ቀን ፡ የሚሠራ ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደል ። ፲፮ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ለልጅ ፡ ልጃቸው ፡ ለዘላለም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ በሰንበት ፡ ያርፉ ፡ ዘንድ ፡ ሰንበትን ፡ ይጠብቁ ። ፲፯ እግዚአብሔር ፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ በስድስት ፡ ቀን ፡ ስለ ፡ ፈጠረ ፥ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ ከሥራው ፡ ስላረፈና ፡ ስለ ፡ ተነፈሰ ፥ በእኔና ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ የዘላለም ፡ ምልክት ፡ ነው ።

፲፰ እግዚአብሔርም ፡ ከሙሴ ፡ ጋር ፡ በሲና ፡ ተራራ ፡ የተናገረውን ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጣት ፡ የተጻፈባቸውን ፡ ከድንጋይ ፡ የሆኑ ፡ ሁለቱን ፡ የምስክር ፡ ጽላቶች ፡ ሰጠው ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

፩ ሕዝቡም ፡ ሙሴ ፡ ከተራራው ፡ ሳይወርድ ፡ እንደ ፡ ዘገየ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፥ ወደ ፡ አሮን ፡ ተሰብሰበው ፡— ይህ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣን ፡ ሰው ፡ ሙሴ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አናውቅምና ፡ ተነሥተህ ፡ በፊታችን ፡ የሚሄዱ ፡ አማልክት ፡ ፪ ሥራልን ፡ አሉት ። አሮንም ፡— በሚስቶቻችሁ ፡ በወንዶችና ፡ በሴቶች ፡ ልጆቻችሁም ፡ ጆሮ ፡ ያሉትን ፡ የወርቅ ፡ ቀለበቶች ፡ ሰብራ ፫ ችሁ ፡ አምጡልኝ ፡ አላቸው ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በጆሮቻቸው ፡ ያሉትን ፡ የወርቅ ፡ ቀለበ ፬ ቶች ፡ ሰብረው ፡ ወደ ፡ አሮን ፡ አመጡለት ። ከእጃቸውም ፡ ተቀብሎ ፡ በመቅረጫ ፡ ቀረጸው ፥ ቀልጦ ፡ የተሠራ ፡ ጥጃም ፡ አደረገው ፤ እርሱም ፡— እስራኤል ፡ ሆይ ፥ እነዚህ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጡህ ፡ አማልክትህ ፡ ናቸው ፡ አሉ ፭ ቸው ። አሮንም ፡ ባየው ፡ ጊዜ ፡ መሠዊያን ፡ በፊቱ ፡ ሠራ ፤ አሮንም ፡— ነገ ፡ የእግዚአብ ፮ ሔር ፡ በዓል ፡ ነው ፡ ሲል ፡ አወጀ ። በነጋውም ፡ ማልደው ፡ ተነሥተው ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዉ ፥ የደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረቡ ፤ ሕዝቡም ፡ ሊበሉና ፡ ሊጠጡ ፡ ተቀመጡ ፥ ሊዘፍኑም ፡ ተነሡ ።

፯ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣኸው ፡ ሕዝብህ ፡ ኃጢአት ፡ ሠርተዋልና ፡ ፰ ሂድ ፥ ውረድ ። ካዘዝኋቸው ፡ መንገድ ፡ ፈጥነው ፡ ፈቀቅ ፡ አሉ ፤ ቀልጦ ፡ የተሠራ ፡ የጥጃ ፡ ምስል ፡ ለራሳቸው ፡ አደረጉ ፥ ሰገዱለትም ፥ ሠዉለትም ፡— እስራኤል ፡ ሆይ ፥ እነዚህ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጡህ ፡ አማልክትህ ፡ ናቸው ፡ አሉ ፡ ሲል ፡ ተናገረው ። ፱ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— እኔ ፡ ይህን ፡ ሕዝብ ፡ አየሁት ፥ እነሆም ፡ አንገተ ፡ ደንዳና ፡ ሕዝብ ፡ ነው ። ፲ አሁንም ፡ ቍጣዬ ፡ እንዲቃጠልባቸው ፡ እንዳጠፋ

ቸውም ፡ ተወኝ ፤ አንተንም ፡ ለታላቅ ፡ ሕዝብ ፡
፲፩ አደርግሃለሁ ፡ አለው ። ሙሴም ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ በአምላኩ ፡ ፊት ፡ ጸለየ ÷ አለም ፡— አቤቱ ÷
ቍጣህ ፡ በታላቅ ፡ ኃይልና ፡ በጽኑ ፡ እጅ ፡ ከግ
ብፅ ፡ ምድር ፡ ስለ ወጣኸው ፡ በሕዝብህ ፡ ላይ ፡
፲፪ ስለ ፡ ምን ፡ ተቃጠለ ? ግብፃውያንስ ፡— በተ
ራራ ፡ መካከል ፡ ሊገድላቸው ÷ ከምድርም ፡
ፊት ፡ ሊያጠፋቸው ፡ ለክፋት ፡ አወጣቸው ፡
ብለው ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይናገራሉ ? ከመዓትህ ፡
ተመለስ ÷ ለሕዝብህም ፡ በክፋታቸው ፡ ላይ ፡
፲፫ ራራ ። ዘራችሁን ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከዋክብት ፡
አበዛለሁ ÷ ይህችንም ፡ የተናገርኋትን ፡ ምድር ፡
ሁሉ ፡ ለዘራችሁ ፡ እሰጣታለሁ ÷ ለዘላለምም ፡
ይወርሱአታል ፡ ብለህ ፡ በራስህ ፡ የማልህላቸ
ውን ፡ ባሪያዎችህን ፡ አብርሃምንና ፡ ይስሐቅን ፡
፲፬ እስራኤልንም ፡ አስብ ። እግዚአብሔርም ፡
በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ሊያደርግ ፡ ስላሰበው ፡ ክፋት ፡
ራራ ።

፲፭ ሙሴም ፡ ተመለሰ ÷ ሁለቱንም ፡ የምስክር ፡
ጽላቶች ፡ በእጁ ፡ ይዞ ፡ ከተራራው ፡ ወረደ ፤
ጽላቶቹም ፡ በዚህና ፡ በዚያ ፡ በሁለት ፡ ወገን ፡
፲፮ ተጽፎባቸው ፡ ነበር ። ጽላቶቹም ፡ የእግዚአ
ብሔር ፡ ሥራ ፡ ነበሩ ፤ ጽሕፈቱም ፡ በጽላቶች ፡
ላይ ፡ የተቀረጸባቸው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጽሕ
፲፯ ፈት ፡ ነበረ ። ኢያሱም ፡ እልል ፡ ሲሉ ፡ የሕዝቡን ፡
ድምፅ ፡ ሰምቶ ፡ ሙሴን ፡— የሰልፍ ፡ ድምፅ ፡
፲፰ በሰፈሩ ፡ ውስጥ ፡ አለ ፡ አለው ። እርሱም ፡—
ይህ ፡ የድል ፡ ነሺዎች ፡ ወይም ፡ የድል ፡ ተነሺ
ዎች ፡ ድምፅ ፡ አይደለም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ የዘፈን ፡
፲፱ ድምፅ ፡ እሰማለሁ ፡ አለው ። እንዲህም ፡ ሆነ ፤
ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ ሲቀርብ ፡ ጥጃውንም ፡ ዘፈኑንም ፡
አየ ፤ የሙሴም ፡ ቍጣ ፡ ተቃጠለ ÷ ጽላቶቹ
ንም ፡ ከእጁ ፡ ጥሎ ፡ ከተራራው ፡ በታች ፡ ሰበ
፳ ራቸው ። የሠሩትንም ፡ ጥጃ ፡ ወስዶ ፡ በእሳት ፡
አቃጠለው ÷ እንደ ፡ ትቢያም ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡
ፈጨው ÷ በውኃውም ፡ ላይ ፡ በተነው ÷ ለእስ
ራኤልም ፡ ልጆች ፡ አጠጣው ።

፳፩ ሙሴም ፡ አሮንን ፡— ይህን ፡ ታላቅ ፡ ኃጢ
አት ፡ ታመጣበት ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ምን ፡
፳፪ አደረገህ ? አለው ። አሮንም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—
ጌታዬ ፡ ሆይ ÷ ቍጣህ ፡ አይቃጠል ፤ ይህ ፡
ሕዝብ ፡ ክፋትን ፡ እንዲወድድ ፡ አንተ ፡ ታው
፳፫ ቃለህ ። እነርሱም ፡— ይህ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡
ያወጣን ፡ ሰው ፡ ሙሴ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እና
ውቅምና ፡ በፊታችን ፡ የሚሄዱ ፡ አማልክት ፡
፳፬ ሥራልን ፡ አሉኝ ። እኔም ፡— ከእናንተ ፡ ወርቅ ፡
ያለው ፡ ሰው ፡ ከእርሱ ፡ ሰብሮ ፡ ያምጣልኝ ፡
አልኋቸው ፤ ሰጡኝም ፤ በእሳትም ፡ ላይ ፡ ጣል
ሁት ÷ ይህም ፡ ጥጃ ፡ ወጣ ።

፳፭ ሙሴም ፡ በጠላቶቻቸው ፡ ፊት ፡ እንዲነወሩ ፡
አሮን ፡ ሰድ ፡ ለቅቋቸዋልና ፡ ሕዝቡ ፡ ሰድ ፡
፳፮ እንደ ፡ ተሰቀቁ ፡ በየ ፡ ጊዜ ÷ በሰፈሩ ፡ ደጅ ፡
ቆሞ ፡— የእግዚአብሔር ፡ ወገን ፡ የሆነ ፡ ወደ ፡
እኔ ፡ ይምጣ ! አለ ፤ የሌዊም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ እርሱ ፡ ተሰበሰቡ ። እርሱም ፡— የእስ ፳፯
ራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— የእናንተ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሰይፉን ፡
በወገቡ ፡ ላይ ፡ ይታጠቅ ፤ በሰፈሩም ፡ ውስጥ ፡
በዚህና ፡ በዚያ ፡ ከበር ፡ እስከ ፡ በር ፡ ተመላለሱ ÷
የእናንተም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ወንድሙን ፡ ወዳጁ
ንም ፡ ጎረቤቱንም ፡ ይግደል ፡ አላቸው ። የሌ ፳፰
ዋም ፡ ልጆች ፡ ሙሴ ፡ እንዳለ ፡ አደረጉ ፤ በዚ
ያም ፡ ቀን ፡ ከሕዝቡ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡
ሞቱ ። ሙሴም ፡— ዛሬ ፡ በረከትን ፡ እንዲያወ ፳፱
ርድላችሁ ፡ እያንዳንዳችሁ ፡ በልጃችሁና ፡ በወ
ንድማችሁ ፡ ላይ ፡ ዛሬ ፡ እጃችሁን ፡ ለእግዚአ
ብሔር ፡ ቀድስ ፤ አድርጉ ፡ አለ ።

በነጋውም ፡ ሙሴ ፡ ለሕዝቡ ፡— እናንተ ፡ ፴
ታላቅ ፡ ኃጢአት ፡ ሠርታችኋል ፤ አሁንም ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እወጣለሁ ፤ ምናልባት ፡
ኃጢአታችሁን ፡ አስተሰርይላችኋለሁ ፡ አላ
ቸው ። ሙሴም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተመ ፴፩
ለሰ ፡— ወዮ ፤ እነዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ታላቅ ፡ ኃጢአት ፡
ሠርተዋል ÷ ለራሳቸውም ፡ የወርቅ ፡ አማል
ክት ፡ አድርገዋል ፤ አሁን ፡ ይህን ፡ ኃጢአታቸ ፴፪
ውን ፡ ይቅር ፡ በላቸው ፤ ያለዚያ ፡ ግን ፡ ከጻፍ
ኸው ፡ መጽሐፍህ ፡ እባክህ ፡ ደምስሰኝ ፡ አለ ።
እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— የበደለኝን ፡ እር ፴፫
ሱን ፡ ከመጽሐፌ ፡ እደመስሰዋለሁ ። አሁንም ፡ ፴፬
ሂድ ÷ ይህንም ፡ ሕዝብ ፡ ወደ ፡ ነገርሁህ ፡ ምራ ፤
እነሆ ፡ መልአኬ ፡ በፊትህ ፡ ይሄዳል ፤ ነገር ፡ ግን ፡
በምጐበኝበት ፡ ቀን ፡ ኃጢአታቸውን ፡ አመጣ
ባቸዋለሁ ፡ አለው ። አሮን ፡ የሠራውን ፡ ጥጃ ፡ ፴፭
ስለ ፡ ሠሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ ቀሠፈ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፫ ።

፩ ፡ ፪ ፡ ፫ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
ተናገረው ፡— ሂድ ÷ ለአብርሃምና ፡ ለይስሐቅ ፡
ለያዕቆብም ፡— ለዘርህ ፡ እሰጣታለሁ ፡ ብዬ ፡ ወደ ፡
ማልሁባት ፡ ምድር ÷ ወተትና ፡ ማርም ፡ ወደም
ታፈስሰው ፡ ምድር ፡ አንተ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡
ከወጣኸው ፡ ሕዝብ ፡ ጋር ፡ ከዚህም ፡ ውጣ ።
አንገተ ፡ ደንዳና ፡ ሕዝብ ፡ ስለ ፡ ሆንህ ፡ በመ
ንገድ ፡ ላይ ፡ እንዳላጠፋህ ፡ እኔ ፡ በአንተ ፡ መካ
ከል ፡ አልወጣምና ፡ በፊትህ ፡ መልአክ ፡ እሰድ
ዳለሁ ፤ ከነዓናዊውን ፡ አሞራዊውንም ፡ ኬጢ
ያዊውንም ፡ ፌርዛዊውንም ፡ ኤዊያዊውንም ፡
ኢያቡሳዊውንም ፡ እወጣልሃለሁ ። ሕዝቡም ፡ ፬
ይህን ፡ ክፉ ፡ ወሬ ፡ ሰምተው ፡ አዘኑ ፤ ከእነር
ሱም ፡ ማንም ፡ ጌጡን ፡ አልለበሰም ። እግዚአ ፭
ብሔርም ፡ ሙሴን ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡—
እናንተ ፡ አንገተ ፡ ደንዳና ፡ ሕዝብ ፡ ናችሁ ÷
አንድ ፡ ጊዜ ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡ ብወጣ ፡
አጠፋችኋለሁ ፤ አሁንም ፡ የማደርግባችሁን ፡
አውቅ ፡ ዘንድ ፡ ጌጣችሁን ፡ ከእናንተ ፡ አውጡ ፡
በላቸው ፡ አለው ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከኮ ፮
ሬብ ፡ ተራራ ፡ ጀምረው ፡ ጌጣቸውን ፡ አወጡ ።
ሙሴም ፡ ድንኳኑን ፡ እየወሰደ ፡ ከሰፈር ፡ ፯

ቸውም ፡ ተወኝ ፤ አንተንም ፡ ለታላቅ ፡ ሕዝብ ፡
፲፩ አደርግሃለሁ ፡ አለው ፡፡ ሙሴም ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ በአምላኩ ፡ ፊት ፡ ጸለየ ፥ አለም ፦ አቤቱ ፥
ቍጣህ ፡ በታላቅ ፡ ኃይልና ፡ በጽኑ ፡ እጅ ፡ ከግ
ብፅ ፡ ምድር ፡ በወጣኸው ፡ በሕዝብህ ፡ ላይ ፡
፲፪ ስለ ፡ ምን ፡ ተቃጠለ ? ግብፃውያንስ ፦ በተ
ራራ ፡ መካከል ፡ ሊገድላቸው ፥ ከምድርም ፡
ፊት ፡ ሊያጠፋቸው ፡ ለክፋት ፡ አወጣቸው ፡
ብለው ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይናገራሉ ? ከመዓትህ ፡
ተመለስ ፥ ለሕዝብህም ፡ በክፋታቸው ፡ ላይ ፡
፲፫ ራራ ፡፡ ዘራችሁን ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከዋክብት ፡
አበዛለሁ ፥ ይህችንም ፡ የተናገርኋትን ፡ ምድር ፡
ሁሉ ፡ ለዘራችሁ ፡ እሰጣታለሁ ፥ ለዘላለምም ፡
ይወርሱአታል ፡ ብለህ ፡ በራስህ ፡ የማልህላቸ
ውን ፡ በሪያዎችህን ፡ አብርሃምንና ፡ ይስሐቅን ፡
፲፬ እስራኤልንም ፡ አስብ ፡፡ እግዚአብሔርም ፡
በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ሊያደርግ ፡ ስላሰበው ፡ ክፋት ፡
ራራ ፡፡

፲፭ ሙሴም ፡ ተመለሰ ፥ ሁለቱንም ፡ የምስክር ፡
ጽላቶች ፡ በእጁ ፡ ይዞ ፡ ከተራራው ፡ ወረደ ፤
ጽላቶቹም ፡ በዚህና ፡ በዚያ ፡ በሁለት ፡ ወገን ፡
፲፮ ተጽፎባቸው ፡ ነበር ፡፡ ጽላቶቹም ፡ የእግዚአ
ብሔር ፡ ሥራ ፡ ነበሩ ፤ ጽሕፈቱም ፡ በጽላቶች ፡
ላይ ፡ የተቀረጸበቸው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጽሕ
፲፯ ፈት ፡ ነበረ ፡፡ ኢያሱም ፡ እልል ፡ ሲሉ ፡ የሕዝቡን ፡
ድምፅ ፡ ሰምቶ ፡ ሙሴን ፦ የሰልፍ ፡ ድምፅ ፡
፲፰ በሰፈሩ ፡ ውስጥ ፡ አለ ፡ አለው ፡፡ እርሱም ፦
ይህ ፡ የድል ፡ ነሺዎች ፡ ወይም ፡ የድል ፡ ተነሺ
ዎች ፡ ድምፅ ፡ አይደለም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ የዘፈን ፡
፲፱ ድምፅ ፡ እሰማለሁ ፡ አለው ፡፡ እንዲህም ፡ ሆነ ፤
ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ ሲቀርብ ፡ ጥጃውንም ፡ ዘፈኑንም ፡
አየ ፤ የሙሴም ፡ ቍጣ ፡ ተቃጠለ ፥ ጽላቶቹ
ንም ፡ ከእጁ ፡ ጥሎ ፡ ከተራራው ፡ በታች ፡ ሰበ
፳ ራቸው ፡፡ የሠሩትንም ፡ ጥጃ ፡ ወስዶ ፡ በእሳት ፡
አቃጠለው ፥ እንደ ፡ ትቢያም ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡
ፈጨው ፥ በውኃውም ፡ ላይ ፡ በተነው ፥ ለእስ
ራኤልም ፡ ልጆች ፡ አጠጣው ፡፡

፳፩ ሙሴም ፡ አሮንን ፦ ይህን ፡ ታላቅ ፡ ኃጢ
አት ፡ ታመጣበት ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ምን ፡
፳፪ አደረገህ ? አለው ፡፡ አሮንም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦
ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ ቍጣህ ፡ አይቃጠል ፤ ይህ ፡
ሕዝብ ፡ ክፋትን ፡ እንዲወድድ ፡ አንተ ፡ ታው
፳፫ ቃለህ ፡፡ እነርሱም ፦ ይህ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡
ያወጣን ፡ ሰው ፡ ሙሴ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አና
ውቅምና ፡ በፊታችን ፡ የሚሄዱ ፡ አማልክት ፡
፳፬ ሥራልን ፡ አሉኝ ፡፡ እኔም ፦ ከእናንተ ፡ ወርቅ ፡
ያለው ፡ ሰው ፡ ከእርሱ ፡ ሰብሮ ፡ ያምጣልኝ ፡
አልኋቸው ፤ ሰጡኝም ፤ በእሳትም ፡ ላይ ፡ ጣል
ሁት ፥ ይህም ፡ ጥጃ ፡ ወጣ ፡፡

፳፭ ሙሴም ፡ በጠላቶቻቸው ፡ ፊት ፡ እንዲነወሩ ፡
አሮን ፡ ስድ ፡ ለቅቋቸዋልና ፡ ሕዝቡ ፡ ስድ ፡
፳፮ እንደ ፡ ተለቀቁ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፥ በሰፈሩ ፡ ደጅ ፡
ቆሞ ፦ የእግዚአብሔር ፡ ወገን ፡ የሆን ፡ ወደ ፡
እኔ ፡ ይምጣ ! አለ ፤ የሌዊም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ እርሱ ፡ ተሰበሰቡ ፡፡ እርሱም ፦ የእስ ፳፯
ራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፦ የእናንተ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሰይፉን ፡
በወገቡ ፡ ላይ ፡ ይታጠቅ ፥ በሰፈሩም ፡ ውስጥ ፡
በዚህና ፡ በዚያ ፡ ከበር ፡ እስከ ፡ በር ፡ ተመላለሱ ፥
የእናንተም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ወንድሙን ፡ ወዳጁ
ንም ፡ ጎረቤቱንም ፡ ይግደል ፡ አላቸው ፡፡ የሌ ፳፰
ዊም ፡ ልጆች ፡ ሙሴ ፡ እንዳለ ፡ አደረጉ ፤ በዚ
ያም ፡ ቀን ፡ ከሕዝቡ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡
ሞቱ ፡፡ ሙሴም ፦ ዛሬ ፡ በረከትን ፡ እንዲያወ ፳፱
ርድላችሁ ፡ እያንዳንዳችሁ ፡ በልጃችሁና ፡ በወ
ንድማችሁ ፡ ላይ ፡ ዛሬ ፡ እጃችሁን ፡ ለእግዚአ
ብሔር ፡ ቀድሱ ፡ አድርጉ ፡ አለ ፡፡

በነጋውም ፡ ሙሴ ፡ ለሕዝቡ ፦ እናንተ ፡ ፴
ታላቅ ፡ ኃጢአት ፡ ሠርታችኋል ፤ አሁንም ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እወጣለሁ ፤ ምናልባት ፡
ኃጢአታችሁን ፡ አስተሰርይላችኋለሁ ፡ አላ
ቸው ፡፡ ሙሴም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተመ ፴፩
ለሰ ፦ ወዮ ! እኒህ ፡ ሕዝብ ፡ ታላቅ ፡ ኃጢአት ፡
ሠርተዋል ፥ ለራሳቸውም ፡ የወርቅ ፡ አማል
ክት ፡ አድርገዋል ፤ አሁን ፡ ይህን ፡ ኃጢአታቸ ፴፪
ውን ፡ ይቅር ፡ በላቸው ፤ ያለዚያ ፡ ግን ፡ ከጻፍ
ኸው ፡ መጽሐፍህ ፡ እባክህ ፡ ደምስሰኝ ፡ አለ ፡፡
እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፦ የበደለኝን ፡ እር ፴፫
ሱን ፡ ከመጽሐፌ ፡ እደመስሰዋለሁ ፡፡ አሁንም ፡ ፴፬
ሂድ ፥ ይህንም ፡ ሕዝብ ፡ ወደ ፡ ነገርሁህ ፡ ምራ ፤
እነሆ ፡ መልአኬ ፡ በፊትህ ፡ ይሄዳል ፤ ነገር ፡ ግን ፡
በምጐበኝበት ፡ ቀን ፡ ኃጢአታቸውን ፡ አመጣ
ባቸዋለሁ ፡ አለው ፡፡ አሮን ፡ የሠራውን ፡ ጥጃ ፡ ፴፭
ስለ ፡ ሠሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ ቀሠፈ ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፴፫ ፡፡

እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፩፡፪፡፫
ተናገረው ፦ ሂድ ፥ ለአብርሃምና ፡ ለይስሐቅ ፡
ለያዕቆብም ፡ ለዘርህ ፡ እሰጣታለሁ ፡ ብዬ ፡ ወደ ፡
ማልሁባት ፡ ምድር ፥ ወተትና ፡ ማርም ፡ ወደም
ታፈስሰው ፡ ምድር ፡ አንተ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡
ከወጣኸው ፡ ሕዝብ ፡ ጋር ፡ ከዚህም ፡ ውጣ ፡፡
አንገተ ፡ ደንዳና ፡ ሕዝብ ፡ ስለ ፡ ሆንህ ፡ በመ
ንገድ ፡ ላይ ፡ እንዳላጠፋህ ፡ እኔ ፡ በአንተ ፡ መካ
ከል ፡ አልወጣምና ፡ በፊትህ ፡ መልአክ ፡ እሰድ
ዳለሁ ፤ ከነዓናዊውን ፡ አሞራዊውንም ፡ ኬጢ
ያዊውንም ፡ ፌርዛዊውንም ፡ ኤዊያዊውንም ፡
ኢያቡሳዊውንም ፡ እወጣልሃለሁ ፡፡ ሕዝቡም ፡ ፬
ይህን ፡ ክፉ ፡ ወሬ ፡ ሰምተው ፡ አዘኑ ፤ ከእነር
ሱም ፡ ማንም ፡ ጌጡን ፡ አላለበሰም ፡፡ እግዚአ ፭
ብሔርም ፡ ሙሴን ፦ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፦
እናንተ ፡ አንገተ ፡ ደንዳና ፡ ሕዝብ ፡ ናችሁ ፥
አንድ ፡ ጊዜ ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡ ብወጣ ፡
አጠፋችኋለሁ ፤ አሁንም ፡ የማደርግባችሁን ፡
አውቅ ፡ ዘንድ ፡ ጌጣችሁን ፡ ከእናንተ ፡ አውጡ ፡
በላቸው ፡ አለው ፡፡ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከኮ ፮
ሬብ ፡ ተራራ ፡ ጀምረው ፡ ጌጣቸውን ፡ አወጡ ፡፡
ሙሴም ፡ ድንኳኑን ፡ እየወሰደ ፡ ከሰፈር ፡ ፯

ውጭ፡ይተክለው፡ነበር፤ እሰፈሩም፡ራቅ፡ያደርገው፡ነበር፤ የመገናኛውም፡ድንኳን፡ብሎ፡ጠራው። እግዚአብሔርንም፡የፈለገ፡ሁሉ፡እሰፈር፡ውጭ፡ወዳለው፡ወደ፡መገናኛው፡ድንኳን፡ይወጣ፡ነበር። ፰ ሙሴም፡ወደ፡ድንኳኑ፡በሄደ፡ጊዜ፡ሕዝቡ፡ሁሉ፡ይነሣ፡ነበር፥እያንዳንዱም፡በድንኳኑ፡ደጃፍ፡ይቆም፡ነበር፥ ሙሴም፡ወደ፡ድንኳኑ፡እስኪገባ፡ድረስ፡ይመለከቱት፡ነበር። ፱ ሙሴም፡ወደ፡ድንኳኑ፡በገባ፡ጊዜ፡የደመና፡ዓምድ፡ይወርድ፡ነበር፥በድንኳኑም፡ደጃፍ፡ይቆም፡ነበር፤ እግዚአብሔርም፡ሙሴን፡ይናገረው፡ነበር። ፲ ሕዝቡም፡ሁሉ፡የደመናው፡ዓምድ፡በድንኳኑ፡ደጃፍ፡ሲቆም፡ያየው፡ነበር፤ ሕዝቡም፡ሁሉ፡ተነሥቶ፡እያንዳንዱ፡በድንኳኑ፡ደጃፍ፡ይሰግድ፡ነበር። ፲፩ እግዚአብሔርም፡ሰው፡ከባልንጀራው፡ጋር፡እንደሚነጋገር፡ፊት፡ለፊት፡ከሙሴ፡ጋር፡ይነጋገር፡ነበር። ሙሴም፡ወደ፡ሰፈሩ፡ይመለስ፡ነበር፤ ነገር፡ግን፡ሎሌው፡ብላቴና፡የነዌ፡ልጅ፡ኢያሱ፡ከድንኳኑ፡አይለይም፡ነበር።

፲፪ ሙሴም፡እግዚአብሔርን፦ እነሆ፡አንተ፦ ይህን፡ሕዝብ፡አውጣ፡ትለኛለህ፤ ከእኔም፡ጋር፡የምትልከውን፡አላስታወቅኸኝም። አንተም፦ በስምህ፡አወቅሁህ፥ደግሞም፡በእኔ፡ፊት፡ሞገስን፡አገኘህ፡አልኸኝ። ፲፫ አሁንም፡በፊትህ፡ሞገስን፡አግኝቼ፡እንደ፡ሆነ፥ አውቅህ፡ዘንድ፡በፊትህም፡ሞገስን፡አገኝ፡ዘንድ፡መንገድህን፡እባክህ፡አሳየኝ፤ ይህም፡ሕዝብ፡ሕዝብህ፡እንደ፡ሆነ፡ተመልከት፡አለው። ፲፬ እግዚአብሔርም፦ እኔ፡ከአንተ፡ጋር፡እሄዳለሁ፥አሳርፍህማለሁ፡አለው። ፲፭ እርሱም፦ አንተ፡ከእኛ፡ጋር፡ካልወጣህስ፥ከዚህ፡አታውጣን። ፲፮ በምድርም፡ፊት፡ካለው፡ሕዝብ፡ሁሉ፡እኔና፡ሕዝብህ፡የተለየን፡እንሆን፡ዘንድ፡አንተ፡ከእኛ፡ጋር፡ካልወጣህ፥ እኔና፡ሕዝብህ፡በአንተ፡ዘንድ፡ሞገስ፡ማግኘታችን፡በምን፡ይታወቃል? አለው።

፲፯ እግዚአብሔርም፡ሙሴን፦ በፊቴ፡ሞገስ፡ስላገኘህ፡በስምህም፡ስላወቅሁህ፡ይህን፡ያልኸውን፡ነገር፡አደርጋለሁ፡አለው። ፲፰ እርሱም፦ እባክህ፡ክብርህን፡አሳየኝ፡አለ። ፲፱ እግዚአብሔርም፦ እኔ፡መልካምነቴን፡ሁሉ፡በፊትህ፡አሳልፋለሁ፤ የእግዚአብሔርንም፡ስም፡በፊትህ፡አውጃለሁ፤ይቅርም፡የምለውን፡ይቅር፡እላለሁ፥የምምረውንም፡እምራለሁ፡አለ። ፳ ደግሞም፦ ሰው፡አይቶኝ፡አይድንምና፡ፊቴን፡ማየት፡አይቻልህም፡አለ። ፳፩ እግዚአብሔርም፡አለ፦ እነሆ፡ስፍራ፡በእኔ፡ዘንድ፡አለ፥ ፳፪ በዓለቱም፡ላይ፡ትቆማለህ፤ ክብሬም፡በሚያልፍ፡ጊዜ፡በሰንጣቃው፡ዓለት፡አኖርሃለሁ፥ እስካልፍ፡ድረስ፡እጄን፡በላይህ፡እጋርዳለሁ፤ ፳፫ እጄንም፡ፈቀቅ፡አደርጋለሁ፥ ጀርባዬንም፡ታያለህ፤ ፊቴ፡ግን፡አይታይም።

## ምዕራፍ፡፴፬።

፩ እግዚአብሔርም፡ሙሴን፡አለው፦ ሁለት፡የድንጋይ፡ጽላቶች፡እንደ፡ፊተኞች፡አድርገህ፡ጥረብ፤ በሰበርኻቸው፡በፊተኞቹ፡ጽላቶች፡የነበሩትን፡ቃሎች፡እጽፍባቸዋለሁ። ፪ ነገም፡የተዘጋጀህ፡ሁን፥ በማለዳም፡ወደ፡ሲና፡ተራራ፡ወጥተህ፡በዚያ፡በተራራው፡ራስ፡ላይ፡በፊቴ፡ቁም። ፫ ካንተም፡ጋር፡ማንም፡ሰው፡አይውጣ፥ በተራራውም፡ሁሉ፡ማንም፡አይታይ፤ መንጎችና፡ከብቶችም፡በዚያ፡ተራራ፡ፊት፡አይሰማሩ። ፬ ሙሴም፡እንደ፡ፊተኞቹ፡አድርጎ፡ሁለት፡የድንጋይ፡ጽላቶች፡ጠረበ፤ በነጋውም፡ማልዶ፡እግዚአብሔር፡እንዳዘዘው፡ወደ፡ሲና፡ተራራ፡ወጣ፥ሁለቱንም፡የድንጋይ፡ጽላቶች፡በእጁ፡ወሰደ። ፭ እግዚአብሔርም፡በደመናው፡ውስጥ፡ወረደ፥ በዚያም፡ከእርሱ፡ጋር፡ቆመ፥ የእግዚአብሔርንም፡ስም፡አወጀ። ፮ እግዚአብሔርም፡በፊቱ፡አልፎ፦ እግዚአብሔር፥ እግዚአብሔር፡መሐሪ፥ሞገስ፡ያለው፥ ታጋሽም፥ባለ፡ብዙ፡ቸርነትና፡እውነት፥ ፯ እስከ፡ሺህ፡ትውልድም፡ቸርነትን፡የሚጠብቅ፥ አበሰንና፡መተላለፍን፡ኃጢአትንም፡ይቅር፡የሚል፥ በደለኛውንም፡ከቶ፡የማያነጻ፥ የአባቶችንም፡ኃጢአት፡በልጆች፡እስከ፡ሦስትና፡እስከ፡አራት፡ትውልድም፡በልጅ፡ልጆች፡የሚያመጣ፡አምላክ፡ነው፡ሲል፡አወጀ። ፰ ሙሴም፡ፈጥኖ፡ወደ፡መሬት፡ተጐነበሰና፡ሰገደ፦ ፱ አቤቱ፡በፊትህስ፡ሞገስን፡አግኝቼ፡እንደ፡ሆነ፥ ይህ፡አንገተ፡ደንዳና፡ሕዝብ፡ነውና፡ጌታዬ፡በመካከላችን፡ይሂድ፤ ጠማማነታችንንና፡ኃጢአታችንንም፡ይቅር፡በለን፥ ስርስትህም፡ተቀበለን፡አለ።

፲ እርሱም፡አለው፦ እነሆ፡እኔ፡ቃል፡ኪዳን፡አደርጋለሁ፤ በምድር፡ሁሉ፥ በአሕዛብም፡ሁሉ፡ዘንድ፡እንደ፡እርሱ፡ያለ፡ከቶ፡ያልተደረገውን፡ተአምራት፡በሕዝብህ፡ሁሉ፡ፊት፡አደርጋለሁ፤ እኔም፡በአንተ፡ዘንድ፡የምሠራው፡ነገር፡የሚያስፈራ፡ነውና፡አንተ፡ያለህበት፡ይህ፡ሕዝብ፡ሁሉ፡የእግዚአብሔርን፡ሥራ፡ያያል። ፲፩ በዚህ፡ቀን፡የማዝዝህን፡ነገር፡ጠብቅ፤ እነሆ፡እኔ፡አሞራዊውን፡ከነዓናዊውንም፡ኬጢያዊውንም፡ፌርዛዊውንም፡ኤዊያዊውንም፡ኢያቡሳዊውንም፡በፊትህ፡አወጣለሁ። ፲፪ በመካከልህ፡ወጥመድ፡እንዳይሆኑብህ፡አንተ፡በምትሄድበት፡ምድር፡ከሚኖሩ፡ሰዎች፡ጋር፡ቃል፡ኪዳን፡እንዳታደርግ፡ተጠንቀቅ፤ ፲፫ ነገር፡ግን፡መሠዊያዎቻቸውን፡ታፈርሳላችሁ፥ ሐውልቶቻቸውንም፡ትሰብራላችሁ፥የማምለኪያ፡ዐፀዶቻቸውንም፡ትቈርጣላችሁ፤ ፲፬ ስሙ፡ቀናተኛ፡የሆነ፡እግዚአብሔር፡ቅንዓት፡ያለው፡አምላክ፡ነውና፡ለሌላ፡አምላክ፡አትስገድ። ፲፭ በዚያች፡ምድር፡ከሚኖሩ፡ሰዎች፡ጋር፡ቃል፡ኪዳን፡እንዳታደርግ፥እን

ርሱ ፡ አምላኮቻቸውን ፡ ተከትለው ፡ በመነዘ ሩና ፡ በሠዉላቸው ፡ ጊዜ ፡ እንዳይጠሩህ ÷ ከመ ፲፮ ሥዋዕታቸውም ፡ እንዳትበላ ÷ ሴት ፡ ልጆቻቸ ውንም ፡ ከወንድ ፡ ልጆችህ ፡ ጋር ፡ እንዳታጋባ ÷ ልጆቻቸውም ፡ አምላኮቻቸውን ፡ ተከትለው ፡ ሲያመነዝሩ ፡ ከአምላኮቻቸው ፡ በኋላ ፡ ሄደው ፡ አመንዝረውም ፡ ልጆችህን ፡ እንዳያስቱ ፡ ተጠ ፲፯ ንቀቅ ። ቀልጠው ፡ የተሠሩትን ፡ የአማልክት ፡ ምስሎች ፡ ለአንተ ፡ አታድርግ ።

፲፰ የቂጣውን ፡ በዓል ፡ ትጠብቀዋለህ ። በአቢብ ፡ ወር ፡ ከግብፅ ፡ ወጥተሃልና ፡ በታዘዘው ፡ ዘመን ፡ በአቢብ ፡ ወር ፡ እንዳዘዝሁህ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ቂጣ ፡ ፲፱ እንጀራ ፡ ብላ ። ማኅፀንንም ፡ የሚከፍት ፡ ሁሉ ፡ የእኔ ፡ ነው ፤ የከብትህም ፡ ተባት ፡ በኵር ፡ ሁሉ ÷ በሬም ፡ ቢሆን ፡ በግም ፡ ቢሆን ÷ የእኔ ፡ ነው ። ፳ የአህያውንም ፡ በኵር ፡ በጠቦት ፡ ትዋጀዋለህ ፤ ባትዋጀውም ፡ አንገቱን ፡ ትሰብረዋለህ ። የል ጆችህንም ፡ በኵር ፡ ሁሉ ፡ ትዋጃለህ ። በፊ ቴም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ባዶ ፡ እጁን ፡ አይታይ ።

፳፩ ስድስት ፡ ቀን ፡ ትሠራለህ ÷ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ ታርፋለህ ፤ በምታርስበትና ፡ በምታጭ ፳፪ ድበት ፡ ዘመን ፡ ታርፋለህ ። የሰባቱንም ፡ሱባዔ ፡ በዓል ፡ ታደርጋለህ ÷ እርሱም ፡ የስንዴ ፡ መከር ፡ በኵራት ፡ ነው ፤ በዓመቱም ፡ ፍጻሜ ፡ የመከ ፳፫ ተቻ ፡ በዓል ፡ ታደርጋለህ ። በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ በእስራኤል ፡ አምላክ ፡ በጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በዓመት ፡ ሦስት ፡ ፳፬ ጊዜ ፡ ይታይ ። አሕዛብን ፡ ከፊትህ ፡ አወጣለሁ ÷ አገርህንም ፡ አሰፋለሁ ፤ በአምላክህም ፡ በእግ ዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለመታየት ፡ በዓመት ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ስትወጣ ፡ ማንም ፡ ምድርህን ፡ አይመኝም ።

፳፭ የመሥዋዕቴን ፡ ደም ፡ ከቦካ ፡ እንጀራ ፡ ጋር ፡ አትሠዋ ፤ የፋሲካውም ፡ በዓል ፡ መሥዋዕት ፡ ፳፮ እስከ ፡ ነገ ፡ አይደር ። የተመረጠውን ፡ የምድ ርህን ፡ ፍሬ ፡ በኵራት ፡ ወደ ፡ አምላክህ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ታገባለህ ። ጠቦቱን ፡ በእ ናቱ ፡ ወተት ፡ አትቀቅልም ።

፳፯ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— በእነዚህ ፡ ቃሎች ፡ መጠን ፡ ከአንተና ፡ ከእስራኤል ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አድርጌአለሁና ፡ እነዚህን ፡ ቃሎች ፡ ፳፰ ጻፍ ፡ አለው ። በዚያም ፡ አርባ ፡ ቀንና ፡ አርባ ፡ ሌሊት ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ ነበረ ፤ እንጀ ራም ፡ አልበላም ÷ ውኃም ፡ አልጠጣም ። በጽ ላቶቹም ፡ አሥሩን ፡ የቃል ፡ ኪዳን ፡ ቃሎች ፡ ጻፈ ።

፳፱ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ሙሴ ፡ ከሲና ፡ ተራራ ፡ በወ ረደ ፡ ጊዜ ፡ ሁለቱ ፡ የምስክር ፡ ጽላቶች ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ ነበሩ ፤ ሙሴም ፡ ከተራራው ፡ በወረደ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ስለ ፡ ተነ ጋገረ ፡ የፊቱ ፡ ቍርበት ፡ እንዳንጸበረቀ ፡ አላወ ፴ ቀም ፡ ነበር ። አሮንና ፡ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ሙሴን ፡ በዩ ፡ ጊዜ ÷ እነሆ ፡ የፊቱ ፡ ቍር በት ፡ እንጸበረቀ ፤ ወደ ፡ እርሱም ፡ ይቀርቡ ፡ ፴፩ ዘንድ ፡ ፈሩ ። ሙሴም ፡ ጠራቸው ፤ አሮንም ፡ የማኅበሩም ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተመለሱ ፤ ሙሴም ፡ ተናገራቸው ። ከዚያም ፡ ፴፪ በኋላ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ቀረቡ ፤ እግ ዚአብሔርም ፡ በሲና ፡ ተራራ ፡ የተነገረውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አዘዛቸው ። ሙሴም ፡ ለእነርሱ ፡ ፴፫ ተናግሮ ፡ ከጨረሰ ፡ በኋላ ፡ በፊቱ ፡ መሸፈኛ ፡ አደረገ ። ሙሴም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሲነጋገር ፡ ፴፬ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ እስኪ ፡ ወጣ ፡ ድረስ ፡ መሸፈኛውን ፡ ከፊቱ ፡ አነሣ ፤ በወጣም ፡ ጊዜ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የታዘዘውን ፡ ነገር ፡ ነገረ ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ የሙሴን ፡ ፊት ፡ ፴፭ ቍርበት ፡ እንዳንጸበረቀ ፡ ያዩ ፡ ነበር ፤ እርሱም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሊነጋገር ፡ እስኪገባ ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ በፊቱ ፡ መሸፈኛ ፡ ያደርግ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፭ ።

፩ ሙሴም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ሰብስቦ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያዘዘው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ፪ ነው ፤ ስድስት ፡ ቀን ፡ ሥራ ፡ ይደረጋል ÷ ሰባ ተኛው ፡ ቀን ፡ ግን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የዕረ ፍት ፡ ሰንበት ፡ የተቀደሰ ፡ ቀን ፡ ይሆንላችኋል ፤ ፫ የሚሠራበትም ፡ ሁሉ ፡ ይገደል ። በማደሪ ያዎቻችሁ ፡ ውስጥ ፡ በሰንበት ፡ ቀን ፡ እሳትን ፡ አታንድዱ ።

፬ ሙሴም ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ አላቸው ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ፭ ብሎ ፡ ያዘዘው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ከእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቍርባንን ፡ አቅርቡ ፤ የልብ ፡ ፈቃድ ፡ ያለው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቍርባን ፡ ያምጣ ፤ ወርቅና ፡ ብርም ፡ ናስም ፤ ፮ ሰማያዊም ፡ ሐምራዊም ፡ ቀይ ፡ ግምጃም ÷ ፯ ጥሩ ፡ በፍታም ÷ የፍየል ፡ ጠጕርም ፤ ቀይም ፡ የአውራ ፡ በግ ፡ ቍርበት ÷ የአቆስጣም ፡ ቍር ፰ ብት ÷ የግራርም ፡ እንጨት ፤ ለመብራትም ፡ ዘይት ÷ ለቅብዓት ፡ ዘይትና ፡ ለጣፋጭ ፡ ዕጣን ፡ ፱ ቅመም ፤ መረግድ ፡ ለኤፉዱና ፡ ለደረት ፡ ኪስ ፡ የሚደረግ ፡ ፈርጥ ፡ ያምጣ ።

፲ በእናንተም ፡ ዘንድ ፡ ያሉ ፡ በልባቸው ፡ ጥበ በኞች ፡ ሁሉ ፡ መጥተው ፡ እግዚአብሔር ፡ ያዘ ፲፩ ዘውን ፡ ሁሉ ፡ ያድርጉ ። ማደሪያውን ÷ ድን ኳኑንም ፡ መደረቢያውንም ÷ መያዣዎቹንም ÷ ሳንቆቹንም ÷ መወርወሪያዎቹንም ÷ ምሰሶቹ ፲፪ ንም ÷ እግሮቹንም ፤ ታቦቱን ፡ መሎጊያዎቹንም ÷ የስርየት ፡ መክደኛውንም ፡ በእርሱም ፡ ፊት ፡ ፲፫ የሚሸፍነውን ፡ መጋረጃ ፤ ገበታውን ፡ መሎ ጊያዎቹንም ፡ ዕቃውንም ፡ ሁሉ ÷ የገጹንም ፡ ፲፬ ኅብስት ፤ መብራት ፡ የሚያበሩበትን ፡ መቅረ ዙን ፡ ዕቃውንም ÷ ቀንዲሉንም ÷ የመብራቱ ፲፭ ንም ፡ ዘይት ፤ የዕጣኑን ፡ መሠዊያም ፡ መሎጊ ያዎቹንም ÷ የቅብዓቱንም ፡ ዘይት ÷ ጣፋጩ ንም ፡ ዕጣን ÷ ለማደሪያውም ፡ ደጃፍ ፡ የሚ ፲፮ ሆን ፡ የደጃፉን ፡ መጋረጃ ፤ ለሚቃጠል ፡ መሥ ዋዕት ፡ የሚሆነውን ፡ መሠዊያውን ÷ የናስ

ንም ፡ መከታ ፥ መሎጊያዎቹንም ፥ እቃውንም ፡ ሁሉ ፤ የመታጠቢያውን ፡ ሰንም ፡ መቀመጫውንም ፤ ፲፯ የአደባባዩን ፡ መጋረጆች ፡ ምሰሶቹንም ፡ እግሮቻቸውንም ፥ የአደባባዩንም ፡ ደጃፍ ፡ ፲፰ መጋረጃ ፤ የማደሪያውን ፡ ካስማዎች ፥ የአደባባዩንም ፡ ካስማዎች ፡ አውታሮቻቸውንም ፤ ፲፱ በመቅደስ ፡ ውስጥ ፡ ለማገልገል ፡ በብልሃት ፡ የተሠሩትን ፡ ልብሶች ፥ በክህነት ፡ ያገለግሉበት ፡ ዘንድ ፡ የተቀደሱትን ፡ የካህኑን ፡ የአሮን ፡ ልብሶች ፥ የልጆቹንም ፡ ልብሶች ።

፳ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ፳፩ ከሙሴ ፡ ፊት ፡ ወጡ ። ከእነርሱም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ልቡ ፡ እንዳነሣሣው ፡ መንፈሱም ፡ እሺ ፡ እንዳሰኘው ፡ ለመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ሥራ ፡ ለማገልገያውም ፡ ሁሉ ፡ ለተቀደሰውም ፡ ልብስ ፡ ፳፪ ለእግዚአብሔር ፡ ስጦታ ፡ አመጡ ። ወንዶችና ፡ ሴቶችም ፡ ልባቸው ፡ እንደ ፡ ፈቀደ ፡ ማርዳዎችን ፥ ሎቲዎችንም ፥ ቀለበቶችንም ፥ ድሪዎችንም ፥ የወርቅ ፡ ጌጦችንም ፡ ሁሉ ፡ አመጡ ፤ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ የወርቅ ፡ ስጦታ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፳፫ አቀረቡ ። ሰማያዊም ፡ ሐምራዊም ፡ ቀይ ፡ ግምጃም ፥ ጥሩ ፡ በፍታም ፥ የፍየል ፡ ጠጕርም ፥ ቀይ ፡ የአውራ ፡ በግ ፡ ቍርበትም ፥ የአቆስጣ ፡ ቍርበትም ፡ ያላቸው ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ አመጡ ። ፳፬ ስእለት ፡ የተሳለ ፡ ሁሉ ፡ የብርንም ፡ የናስንም ፡ ስጦታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቍርባን ፡ አቀረበ ፤ የግራርም ፡ እንጨት ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ ለማገል ፳፭ ገያ ፡ ሥራ ፡ አመጣ ። በልባቸው ፡ ጥበበኞች ፡ የሆኑ ፡ ሴቶችም ፡ በእጃቸው ፡ ፈተሉ ፥ የፈተሉትንም ፡ ሰማያዊውን ፡ ሐምራዊውንም ፡ ቀዩንም ፡ ግምጃ ፥ ጥሩውንም ፡ በፍታ ፡ አመጡ ። ፳፮ ልባቸውም ፡ በጥበብ ፡ ያስነሣቸው ፡ ሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ፳፯ የፍየልን ፡ ጠጕር ፡ ፈተሉ ። አለቆችም ፡ መረግዶን ፥ ለኤፉድና ፡ ለደረት ፡ ኪስ ፡ የሚገቡትንም ፡ ፳፰ ፈርጦችን ፥ ለመብራትም ፡ ለቅብዓት ፡ ዘይትም ፡ ለጣፋጭ ፡ ዕጣንም ፡ ሽቱንና ፡ ዘይትን ፡ አመጡ ። ፳፱ ከእስራኤል ፡ ልጆችም ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡ ልባቸው ፡ ያስነሣቸው ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ሙሴ ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ላዘዘው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስጦታ ፡ በፈቃዳቸው ፡ አመጡ ።

፴ ሙሴም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ አላቸው ፦ እዩ ፥ እግዚአብሔር ፡ ከይሁዳ ፡ ነገድ ፡ የሆነውን ፡ የሆር ፡ የልጅ ፡ ልጅ ፥ የኡሪ ፡ ልጅ ፡ ባስ ፴፩ ልኤልን ፡ በስሙ ፡ ጠራው ። በሥራ ፡ ሁሉ ፡ ብልሃት ፡ በጥበብም ፡ በማስተዋልም ፡ በእውቀትም ፡ ፴፪ የእግዚአብሔርን ፡ መንፈስ ፡ ሞላበት ፤ የጥበብን ፡ ሥራ ፡ ያስተውል ፡ ዘንድ ፥ በወርቅና ፡ ፴፫ በብር ፡ በናስም ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፥ በፈርጥ ፡ የሚሆነውን ፡ የዕንቍ ፡ ድንጋይ ፡ ይቀርጽ ፡ ዘንድ ፥ እንጨቱንም ፡ ይጠርብ ፡ ዘንድ ፥ የብልሃት ፡ ሥራውንም ፡ ሁሉ ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ። ፴፬ እርሱና ፡ የዳን ፡ ነገድ ፡ የሆነው ፡ የአሂሳሚክ ፡ ልጅ ፡ ኤልያብ ፡ ያስተምሩ ፡ ዘንድ ፡ በልባቸው ፡ ፴፭ አሳደረባቸው ። በእንጥረኛ ፥ በብልሀ ፡ ሠራተኛም ፥ በሰማያዊና ፡ በሐምራዊ ፡ በቀይም ፡ ግምጃ ፡ በጥሩ ፡ በፍታም ፡ በሚሠራ ፡ ጠላፊ ፥ በሸማኔም ፡ ሥራ ፡ የሚሠራውን ፥ ማናቸውንም ፡ ሥራና ፡ በብልሃት ፡ የሚሠራውን ፡ ሁሉ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ በእነርሱ ፡ ልብ ፡ ጥበብን ፡ ሞላ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፮ ።

፩ ለመቅደስም ፡ ማገልገያ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ እንዲያውቁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጥበብንና ፡ ማስተዋልን ፡ የሰጣቸው ፡ ባስልኤልና ፡ ኤልያብ ፡ በልባቸው ፡ ጥበበኞችም ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አደረጉ ።

፪ ሙሴም ፡ ባስልኤልንና ፡ ኤልያብን ፥ እግዚአብሔርም ፡ በልቡ ፡ ጥበብን ፡ ያደረገለትን ፡ በልብ ፡ ጥበበኛ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፥ ሥራውንም ፡ ለመሥራት ፡ ይቀርብ ፡ ዘንድ ፡ ልቡ ፡ ያስነሣውን ፡ ሁሉ ፡ ጠራቸው ። ፫ እነርሱም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ለመቅደስ ፡ ማገልገያ ፡ ሥራ ፡ ያመጡትን ፡ ስጦታ ፡ ሁሉ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ከሙሴ ፡ ተቀበሉ ። እነዚያም ፡ እንደ ፡ ፈቃዳቸው ፡ ማለዳ ፡ ማለዳ ፡ ስጦታውን ፡ ገና ፡ ወደ ፡ ፬ እርሱ ፡ ያመጡ ፡ ነበር ። የመቅደሱንም ፡ ሥራ ፡ የሚሠሩ ፡ ጠቢባን ፡ ሁሉ ፡ የሚያደርጉትን ፡ ፭ ሥራ ፡ ትተው ፡ መጡ ፥ እነርሱም ፡ ሙሴን ፦ እግዚአብሔር ፡ ለማገልገያ ፡ ሥራ ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ ላዘዘው ፡ ከሚበቃ ፡ ይልቅ ፡ እጅግ ፡ የሚበልጥ ፡ ሕዝቡ ፡ አመጡ ፡ ብለው ፡ ተናገሩት ። ፮ ፤ ፯ ያመጡትም ፡ ነገር ፡ ሥራን ፡ ሁሉ ፡ ለመፈጸም ፡ በቂ ፡ ገና ፡ ይተርፍ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ሙሴ ፡ አዘዘና ፦ ወንድ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ለመቅደስ ፡ ስጦታ ፡ ከዚህ ፡ የበለጠ ፡ የሚያመጣ ፡ አይኑር ፡ ብሎ ፡ በሰፈሩ ፡ ውስጥ ፡ አሳወጀ ። ሕዝቡም ፡ እንዳያመጡ ፡ ተከለከሉ ።

፰ በእነርሱም ፡ ዘንድ ፡ ያሉት ፡ ሥራ ፡ ሲሠሩ ፡ የነበሩት ፡ በልባቸው ፡ ጥበበኞች ፡ ሁሉ ፡ ማደሪያውን ፡ ከአሥር ፡ መጋረጆች ፡ ሠሩ ፤ እነርሱንም ፡ ከተፈተለ ፡ ከጥሩ ፡ በፍታ ፥ ከሰማያዊም ፡ ከሐምራዊም ፡ ከቀይም ፡ ግምጃ ፡ ሠሩ ፤ በእነርሱም ፡ ላይ ፡ ብልሀ ፡ ሠራተኛ ፡ እንደሚሠራ ፡ ፱ ኪሩቤልን ፡ አደረጉባቸው ። የእያንዳንዱ ፡ መጋረጃ ፡ ርዝመት ፡ ሀያ ፡ ስምንት ፡ ክንድ ፥ ወርዱም ፡ አራት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፤ የመጋረጆቹ ፡ ፲ ሁሉ ፡ ልክ ፡ ትክክል ፡ ነበረ ። አምስቱንም ፡ መጋረጆች ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ አጋጠሙ ፤ አምስቱንም ፡ መጋረጆች ፡ እንዲሁ ፡ እርስ ፡ በርሳ ፲፩ ቸው ፡ አጋጠሙ ። ከሚጋጠሙትም ፡ መጋረጆች ፡ በአንደኛው ፡ መጋረጃ ፡ ዘርፍ ፡ ላይ ፡ የሰማያዊውን ፡ ግምጃ ፡ ቀለበቶች ፡ አደረጉ ፤ ደግሞ ፡ ከተጋጠሙት ፡ ከሌሎቹ ፡ በአንደኛው ፡ መጋረጃ ፡ ዘርፍ ፡ ላይ ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ። ፲፪ አምሳ ፡ ቀለበቶችን ፡ በአንድ ፡ መጋረጃ ፡ አደ

ረጉ ፤ አምሳውንም ፡ ቀለበቶች ፡ በሁለተኛው ፡
መጋረጃ ፡ ዘርፍ ፡ አደረጉ ፤ ቀለበቶቹ ፡ እርስ ፡
በርሳቸው ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ የሚተያዩ ፡ ነበሩ ።
፲፫ እምሳም ፡ የወርቅ ፡ መያዣዎች ፡ ሠሩ ፤ መጋ
ረጆችንም ፡ እርስ ፡ በርስቸው ፡ በመያዣዎች ፡
አጋጠሙአቸው ፤ አንድ ፡ ማደሪያም ፡ ሆነ ።
፲፬ ከማደሪያውም ፡ በላይ ፡ ለድንኳን ፡ የሚሆኑ ፡
መጋረጆችን ፡ ከፍየል ፡ ጠጕር ፡ አደረጉ ፤
፲፭ አሥራ ፡ አንድ ፡ መጋረጆች ፡ አደረጉ ። እያን
ዳንዱም ፡ መጋረጃ ፡ ርዝመቱ ፡ ሠላሳ ፡ ክንድ ፥
እያንዳንዱም ፡ መጋረጃ ፡ ወርዱ ፡ አራት ፡ ክንድ ፡
ነበረ ፤ የአሥራ ፡ አንዱም ፡ መጋረጆች ፡ መጠ
፲፮ ናቸው ፡ ትክክል ፡ ነበረ ። አምስቱንም ፡ መጋ
ረጆች ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ አንድ ፡ አድርገው ፥
ስድስቱንም ፡ መጋረጆች ፡ አንድ ፡ አድርገው ፡
፲፯ አጋጠሙአቸው ። ከተጋጠሙትም ፡ መጋረ
ጆች ፡ በአንደኛው ፡ መጋረጃ ፡ ዘርፍ ፡ ላይ ፡
አምሳ ፡ ቀለበቶች ፡ አደረጉ ፤ ደግሞ ፡ ከተጋጠ
ሙት ፡ ከሌሎቹ ፡ በአንደኛው ፡ መጋረጃ ፡ ዘርፍ ፡
፲፰ ላይ ፡ አምሳ ፡ ቀለበቶች ፡ አደረጉ ። ድንኳኑም ፡
አንድ ፡ እንዲሆን ፡ ያጋጥሙት ፡ ዘንድ ፡ አምሳ ፡
፲፱ የናስ ፡ መያዣዎችን ፡ ሠሩ ። ለድንኳኑም ፡
መደረቢያ ፡ ከቀይ ፡ ከአውራ ፡ በግ ፡ ቁርበት ፥
ከዚያም ፡ በላይ ፡ ሌላ ፡ መደረቢያ ፡ ከአቆስጣ ፡
ቁርበት ፡ አደረጉ ።

፳ ለማደሪያውም ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ የሚቆ
፳፩ ሙትን ፡ ሳንቆች ፡ አደረጉ ። የሳንቃው ፡ ሁሉ ፡
ርዝመቱ ፡ አሥር ፡ ክንድ ፥ ወርዱም ፡ አንድ ፡
፳፪ ክንድ ፡ ተኩል ፡ ነበረ ። ለእያንዳንዱም ፡ ሳንቃ ፡
አንዱን ፡ በአንዱ ፡ ላይ ፡ የሚያያይዙ ፡ ሁለት ፡
ማጋጠሚያዎች ፡ ነበሩ ፤ ለማደሪያው ፡ ሳን
፳፫ ቆች ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ። ለማደሪያ
ውም ፡ በደቡብ ፡ ወገን ፡ ሀያ ፡ ሳንቆችን ፡ አደረጉ ፤
፳፬ ከሀያውም ፡ ሳንቆች ፡ በታች ፡ አርባ ፡ የብር ፡
እግሮች ፡ አደረጉ ፤ ከእያንዳንዱም ፡ ሳንቃ ፡
በታች ፡ ለሁለቱ ፡ ማጋጠሚያዎች ፡ ሁለት ፡ እግ
፳፭ ሮች ፡ ነበሩ ። ለማደሪያው ፡ ለሁለተኛው ፡ ወገን ፡
በሰሜን ፡ በኩል ፡ ሀያ ፡ ሳንቆች ፡ አደረጉ ፤
፳፮ ለእነርሱም ፡ አርባ ፡ የብር ፡ እግሮች ፥ ከእያን
ዳንዱም ፡ ሳንቃ ፡ በታች ፡ ሁለት ፡ እግሮች ፡
፳፯ አደረጉ ። ለማደሪያውም ፡ በምዕራብ ፡ ወገን ፡
በስተ ፡ ኋላ ፡ ስድስት ፡ ሳንቆች ፡ አደረጉ ።
፳፰ ለማደሪያውም ፡ ለሁለቱ ፡ ማዕዘን ፡ በስተ ፡ ኋላ ፡
፳፱ ሁለት ፡ ሳንቆች ፡ አደረጉ ። ከታችም ፡ እስከ ፡
ላይ ፡ እስከ ፡ አንደኛው ፡ ቀለበት ፡ ድረስ ፡ አንድ ፡
ሳንቃ ፡ ድርብ ፡ ነበረ ፤ ለሁለቱም ፡ ማዕዘን ፡ እን
፴ ዲሁ ፡ ሁለት ፡ ነበሩ ። ስምንት ፡ ሳንቆችና ፡
አሥራ ፡ ስድስቱ ፡ የብር ፡ እግሮቻቸው ፥ ከእያ
ንዳንዱም ፡ ሳንቃ ፡ በታች ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ እግ
ሮች ፡ ነበሩ ።

፴፩ ከግራርም ፡ እንጨት ፡ በማደሪያው ፡ በአንደ
ኛው ፡ ወገን ፡ ላሉት ፡ ሳንቆች ፡ አምስት ፡ መወ
፴፪ ርወሪያዎች ፥ በማደሪያውም ፡ በሁለተኛው ፡
ወገን ፡ ላሉት ፡ ሳንቆች ፡ አምስት ፡ መወርወሪያ
ዎች ፥ ከማደሪያውም ፡ በስተ ፡ ኋላ ፡ በምዕራብ ፡
ወገን ፡ ላሉት ፡ ሳንቆች ፡ አምስት ፡ መወርወ
፴፫ ሪያዎች ፡ አደረጉ ። መካከለኛውንም ፡ መወር
ወሪያ ፡ በሳንቆቹ ፡ መካከል ፡ ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡
፴፬ አሳለፉ ። ሳንቆቹንም ፡ በወርቅ ፡ ለበጡአቸው ፤
ቀለበቶቻቸውንም ፡ የመወርወሪያ ፡ ቤት ፡ እን
ዲሆኑላቸው ፡ ከወርቅ ፡ አደረጉ ፤ መወርወሪያ
ዎቹንም ፡ በወርቅ ፡ ለበጡአቸው ።
፴፭ መጋረጃውንም ፡ ከሰማያዊና ፡ ከሐምራዊ ፡
ከቀይም ፡ ግምጃ ፥ ከተፈተለም ፡ ከጥሩ ፡ በፍታ ፡
አደረጉ ፤ ብልሀ ፡ ሠራተኛ ፡ እንደሚሠራ ፡ ኪሩ
፴፮ ቤልን ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ አደረጉ ። ከግራርም ፡
እንጨት ፡ አራት ፡ ምሰሶች ፡ አደረጉለት ፥ በወ
ርቅም ፡ ለበጡአቸው ፤ ኩላቦቻቸው ፡ የወርቅ ፡
ነበሩ ፤ ለእነርሱም ፡ አራት ፡ የብር ፡ እግሮች ፡
፴፯ አደረጉ ። ለድንኳኑም ፡ ደጃፍ ፡ ከሰማያዊና ፡
ከሐምራዊ ፡ ከቀይም ፡ ግምጃ ፥ ከተፈተለም ፡
ከጥሩ ፡ በፍታ ፡ በጥልፍ ፡ አሠራር ፡ የተሠራ ፡
፴፰ መጋረጃ ፡ አደረጉ ፤ አምስቱንም ፡ ምሰሶች ፥
ኩላቦቻቸውንም ፡ አደረጉ ፤ ጕልላቶቻቸው
ንና ፡ ዘንጎቻቸውንም ፡ በወርቅ ፡ ለበጡአቸው ፤
አምስቱም ፡ እግሮቻቸው ፡ የናስ ፡ ነበሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፯ ።

፩ ባስልኤልም ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ ታቦቱን ፡
ሠራ ፤ ርዝመቱም ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፡ ተኩል ፥
ወርዱም ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ተኩል ፥ ቁመቱም ፡
፪ አንድ ፡ ክንድ ፡ ተኩል ፡ ነበረ ። በውስጥም ፡
በውጭም ፡ በጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ለበጠው ፤ በዙሪያ
፫ ውም ፡ የወርቅ ፡ አክሊል ፡ አደረገለት ። አራት ፡
የወርቅ ፡ ቀለበቶችም ፡ አደረገለት ፤ እነርሱ
ንም ፡ በአራቱ ፡ እግሮቹ ፡ ላይ ፡ አኖረ ። በአ
ንድ ፡ ወገን ፡ ሁለት ፡ ቀለበቶች ፥ በሌላውም ፡
፬ ወገን ፡ ሁለት ፡ ቀለበቶች ፡ ሆኑ ። መሎጊያዎ
ቹንም ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ ሠራ ፥ በወርቅም ፡
፭ ለበጣቸው ። ታቦቱንም ፡ ለመሸከም ፡ በታቦቱ ፡
አጠገብ ፡ ባሉት ፡ ቀለበቶች ፡ መሎጊያዎቹን ፡
፮ አገባ ። ከጥሩ ፡ ወርቅም ፡ ርዝመቱ ፡ ሁለት ፡
ክንድ ፡ ተኩል ፥ ወርዱም ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡
ተኩል ፡ የሆነ ፡ የስርየት ፡ መክደኛ ፡ ሠራ ።
፯ ሁለት ፡ ኪሩቤልንም ፡ ከተቀጠቀጠ ፡ ወርቅ ፡
ሠራ ፤ በስርየት ፡ መክደኛውም ፡ ላይ ፡ በሁለት ፡
፰ ወገን ፡ አደረጋቸው ። ከስርየት ፡ መክደኛ
ውም ፡ ጋር ፡ አንዱን ፡ ኪሩብ ፡ በአንድ ፡ ወገን ፥
ሁለተኛውንም ፡ ኪሩብ ፡ በሌላው ፡ ወገን ፡ አድ
፱ ርጎ ፡ በአንድ ፡ ላይ ፡ ሠራቸው ። ኪሩቤልም ፡
ክንፎቻቸውን ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ የዘረጉ ፡ ሆኑ ፥ የስር
የት ፡ መክደኛውንም ፡ በክንፎቻቸው ፡ ሸፈኑ ፥
እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ ተያዩ ፤ የኪሩቤልም ፡
ፊቶቻቸው ፡ ወደ ፡ መክደኛው ፡ ተመለከቱ ።
፲ ርዝመቱ ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፥ ወርዱም ፡ አንድ ፡
ክንድ ፥ ቁመቱም ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ተኩል ፡
የሆነውን ፡ ገበታ ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ ሠራ ።
፲፩ በጥሩም ፡ ወርቅ ፡ ለበጠው ፥ በዙሪያውም ፡

፲፪ የወርቅ ፡ አክሊል ፡ አደረገለት ። በዙሪያውም ፡
አንድ ፡ ጋት ፡ የሚያህል ፡ ክፈፍ ፡ አደረገለት ፤
የወርቅም ፡ አክሊል ፡ በክፈፉ ፡ ዙሪያ ፡ አደረገ
፲፫ ለት ። አራትም ፡ የወርቅ ፡ ቀለበቶች ፡ አደረ
ገለት ፤ ቀለበቶቹንም ፡ አራቱ ፡ እግሮቹ ፡ ባሉ
፲፬ በት ፡ በአራቱ ፡ ማዕዘኖች ፡ አደረገ ። ገበታው
ንም ፡ ለመሸከም ፡ መሎጊያዎቹ ፡ እንዲሸኩባ
ቸው ፡ ቀለበቶች ፡ በክፈፉ ፡ አቅራቢያ ፡ ነበሩ ።
፲፭ ገበታውንም ፡ ይሸከሙባቸው ፡ ዘንድ ፡ መሎ
ጊያዎቹን ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ ሠርቶ ፡ በወ
፲፮ ርቅ ፡ ለበጣቸው ። ለማፍሰሻም ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡
በገበታው ፡ ላይ ፡ የሚኖሩትን ፡ ዕቃዎች ፥ ወጭ
ቶቹንና ፡ ጭልፋዎቹን ፡ ጽዋዎቹንም ፡ መቅ
ጃዎቹንም ፥ ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ አደረጋቸው ።

፲፯ መቅረዙንም ፡ ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ አደረገ ፤ መቅ
ረዙንም ፡ ከእግሩና ፡ ከአገዳው ፡ ጋር ፡ በተቀረጸ ፡
ሥራ ፡ አደረገ ፤ ጽዋዎቹን ፥ ጕብጕቦቹን ፥ አበ
፲፰ ቦቹን ፡ ከዚያው ፡ በአንድነት ፡ አደረገ ። በስተ
ጐኑም ፡ ስድስት ፡ ቅርንጫፎች ፡ ወጡለት ፤
ሦስቱ ፡ የመቅረዙ ፡ ቅርንጫፎች ፡ በአንድ ፡
ወገን ፥ ሦስቱም ፡ የመቅረዙ ፡ ቅርንጫፎች ፡
፲፱ በሌላ ፡ ወገን ፡ ወጡ ። በአንደኛው ፡ ቅርንጫፍ ፡
ጕብጕቡንና ፡ አበባውን ፡ ሦስትም ፡ የለውዝ ፡
አበባ ፡ የሚመስሉትን ፡ ጽዋዎች ፥ በሁለተኛ
ውም ፡ ቅርንጫፍ ፡ ጕብጕቡንና ፡ አበባውን ፡
ሦስትም ፡ የለውዝ ፡ አበባ ፡ የሚመስሉትን ፡
ጽዋዎች ፥ እንዲሁም ፡ ከመቅረዙ ፡ ለወጡ ፡
፳ ለስድስቱ ፡ ቅርንጫፎች ፡ አደረገ ። በመቅረ
ዙም ፡ ጕብጕቦቹንና ፡ አበቦቹን ፡ አራትም ፡
የለውዝ ፡ አበባ ፡ የሚመስሉትን ፡ ጽዋዎች ፡
፳፩ አደረገ ። ከመቅረዙ ፡ ለወጡ ፡ ለስድስት ፡ ቅር
ንጫፎች ፡ ከሁለት ፡ ቅርንጫፎች ፡ በታች ፡
አንድ ፡ ሆኖ ፡ የተሠራ ፡ አንድ ፡ ጕብጕብ ፥ ከሁ
ለትም ፡ ቅርንጫፎች ፡ በታች ፡ አንድ ፡ ሆኖ ፡
የተሠራ ፡ አንድ ፡ ጕብጕብ ፥ ደግሞ ፡ ከሁለት ፡
ቅርንጫፎች ፡ በታች ፡ አንድ ፡ ሆኖ ፡ የተሠራ ፡
፳፪ አንድ ፡ ጕብጕብ ፡ ነበረ ። ጕብጕቦቹና ፡ ቅርን
ጫፎቹ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ነበሩ ፤ ሁሉም ፡
አንድ ፡ ሆኖ ፡ ከተቀረጸ ፡ ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ተሠ
፳፫ ርቶ ፡ ነበር ። ሰባቱንም ፡ መብራቶች ፡ መኰስ
ተሪያዎቹንም ፥ የኩስታሪ ፡ ማድረጊያዎቹንም ፡
፳፬ ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ሠራ ። መቅረዙንም ፡ ዕቃው
ንም ፡ ሁሉ ፡ ከአንድ ፡ መክሊት ፡ ጥሩ ፡ ወርቅ ፡
አደረገ ።

፳፭ የዕጣን ፡ መሠዊያ ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ ሠራ ፤
ርዝመቱ ፡ አንድ ፡ ክንድ ፥ ስፋቱ ፡ አንድ ፡ ክንድ ፥
አራት ፡ ማዕዘን ፡ ነበረ ፤ ከፍታውም ፡ ሁለት ፡
ክንድ ፡ ነበረ ፤ ቀንዶቹም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በአ
፳፮ ንድነት ፡ የተሠሩ ፡ ነበሩ ። ላይኛውንና ፡ የግ
ድግዳውንም ፡ ዙሪያ ፡ ቀንዶቹንም ፡ በጥሩ ፡
ወርቅ ፡ ለበጠው ፤ በዙሪያውም ፡ የወርቅ ፡ ክፈፍ ፡
፳፯ አደረገበት ። ከክፈፉም ፡ በታች ፡ ሁለት ፡ የወ
ርቅ ፡ ቀለበቶች ፡ አደረገበት ፥ በዚህና ፡ በዚያ ፡
በሁለቱም ፡ ጐን ፡ አደረጋቸው ፤ ለመሸከምም ፡
፳፰ የመሎጊያዎች ፡ ስፍራ ፡ ነበሩ ። መሎጊያዎቹ
ንም ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ አደረገ ፥ በወርቅም ፡
፳፱ ለበጣቸው ። የተቀደሰውንም ፡ የቅብዓቱን ፡
ዘይት ፥ ጥሩውንም ፡ የጣፋጭ ፡ ሽቱ ፡ ዕጣን ፡
በቀማሚ ፡ ብልሃት ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፡ አደረገ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፰ ።

፩ ርዝመቱ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፥ ወርዱም ፡ አም
ስት ፡ ክንድ ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የሚ
ሆን ፡ መሠዊያን ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ አደረገ ፤
አራት ፡ ማዕዘንም ፡ ነበረ ፤ ከፍታው ፡ ሦስት ፡
፪ ክንድ ፡ ነበረ ። ቀንዶቹንም ፡ በአራቱ ፡ ማዕዘን ፡
አደረገበት ፤ ቀንዶቹም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በአ
ንድ ፡ የተሠሩ ፡ ነበሩ ፤ በናስም ፡ ለበጠው ።
፫ የመሠዊያውንም ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፥ ምንቸቶቹንም ፥
መጫሪያዎቹንም ፥ ድስቶቹንም ፥ ሜንጦቹ
ንም ፥ ማንደጃዎቹንም ፡ አደረገ ፤ ዕቃውንም ፡
፬ ሁሉ ፡ ከናስ ፡ አደረገ ። እንደ ፡ መረብ ፡ ሆኖም ፡
የተሠራ ፡ የናስ ፡ መከታ ፡ ለመሠዊያ ፡ አደረገ ፤
መከታውም ፡ እስከ ፡ መሠዊያው ፡ እኩሌታ ፡
ይደርስ ፡ ዘንድ ፡ በመሠዊያው ፡ በሚዞረው ፡
፭ በደረጃው ፡ ታች ፡ አደረገው ። ለናሱም ፡ መከታ ፡
ለአራቱ ፡ ማዕዘን ፡ የመሎጊያዎች ፡ ስፍራ ፡
ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ አራት ፡ ቀለበቶች ፡ አደረገ ።
፮ መሎጊያዎቹንም ፡ ከግራር ፡ እንጨት ፡ ሠራ ፥
፯ በናስም ፡ ለበጣቸው ። ይሸከሙትም ፡ ዘንድ ፡
በመሠዊያ ፡ ጐን ፡ ባሉት ፡ ቀለበቶች ፡ ውስጥ ፡
መሎጊያዎቹን ፡ አገባ ፤ ከሳንቆቹም ፡ ሠርቶ ፡
ባዶ ፡ አደረገው ።

፰ የመታጠቢያውን ፡ ሰንና ፡ መቀመጫውንም ፡
በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ከሚያገለግሉ ፡
ከሴቶች ፡ መስተዋት ፡ ከናስ ፡ አደረገ ።

፱ አደባባዩንም ፡ አደረገ ፤ በደቡብ ፡ ወገን ፡ ርዝ
መቱ ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፥ የተፈተለ ፡ የጥሩ ፡
፲ በፍታ ፡ መጋረጆች ፡ ነበሩ ። ከናስ ፡ የተሠሩ ፡
ሀያውን ፡ ምሰሶችና ፡ ሀያውን ፡ እግሮች ፡ አደ
ረገ ፤ የምሰሶቹንም ፡ ኩላቦችና ፡ ዘንጎች ፡ ከብር ፡
፲፩ አደረገ ። በስሜኑም ፡ ወገን ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡
ርዝመት ፡ ያላቸውን ፡ መጋረጆች ፥ ከናስም ፡ የተ
ሠራ ፡ ሀያ ፡ ምሰሶችንና ፡ ሀያ ፡ እግሮችን ፥ ለም
ሰሶቹም ፡ የብር ፡ ኩላቦችንና ፡ ዘንጎችን ፡ አደ
፲፪ ረገ ። በምዕራብም ፡ ወገን ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ርዝ
መት ፡ ያላቸውን ፡ መጋረጆች ፥ አሥሩንም ፡
ምሰሶች ፥ አሥሩንም ፡ የናስ ፡ እግሮች ፥ ለምስ
ሶቹም ፡ የብር ፡ ኩላቦችንና ፡ ዘንጎችን ፡ አደረገ ።
፲፫ በምሥራቅም ፡ ወገን ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ርዝመት ፡
፲፬ ያላቸውን ፡ መጋረጆች ፡ አደረገ ። በአንድ ፡
ወገንም ፡ የመጋረጆቹ ፡ ርዝመት ፡ አሥራ ፡ አም
ስት ፡ ክንድ ፥ ምሰሶቹም ፡ ሦስት ፥ እግሮቹም ፡
፲፭ ሦስት ፡ ነበሩ ። እንዲሁም ፡ በሁለተኛው ፡ ወገን ፤
በአደባባዩ ፡ ደጅ ፡ በዚህና ፡ በዚያ ፡ አሥራ ፡ አም
ስት ፡ ክንድ ፡ ርዝመት ፡ ያላቸው ፡ መጋረጆች ፥
ሦስትም ፡ ምሰሶች ፥ ሦስትም ፡ እግሮች ፡ ነበሩ ።
፲፮ በአደባባዩ ፡ ዙሪያ ፡ ያሉ ፡ መጋረጆች ፡ ሁሉ ፡

ከተፈተለ ፡ ከጥሩ ፡ በፍታ ፡ ተሠርተው ፡ ነበር ። ፲፯ የምሰሶቹም ፡ እግሮች ፡ የናስ ፥ የምሰሶቹም ፡ ኩላቦችና ፡ ዘንጎች ፡ የብር ፡ ነበሩ ፤ የምሰሶችም ፡ ጕልላቶች ፡ በብር ፡ ተለብጠው ፡ ነበር ፤ በአደባባዩ ፡ ላሉ ፡ ምሰሶች ፡ ሁሉ ፡ የብር ፡ ዘንጎች ፡ ነበሩአቸው ። ፲፰ የአደባባዩም ፡ ደጅ ፡ መጋረጃ ፡ ከሰማያዊ ፡ ከሐምራዊም ፡ ከቀይም ፡ ግምጃ ፥ ከጥሩም ፡ በፍታ ፡ በጥልፍ ፡ አሠራር ፡ የተሠራ ፡ ነበረ ፤ ርዝመቱ ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ ቁመቱም ፡ እንደ ፡ አደባባዩ ፡ መጋረጆች ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፤ ፲፱ ከናስ ፡ የተሠሩ ፡ ምሰሶቹም ፡ አራት ፥ እግሮቹም ፡ አራት ፡ ነበሩ ፤ ኩላቦቹ ፡ የብር ፡ ነበሩ ፤ ጕልላቶቹና ፡ ዘንጎቹም ፡ በብር ፡ ተለብጠው ፡ ነበር ። ፳ የማደሪያውም ፡ ካስማዎች ፡ በዙሪያውም ፡ ያለ ፡ የአደባባዩ ፡ ካስማዎች ፡ የናስ ፡ ነበሩ ።

፳፩ በሙሴ ፡ ትእዛዝ ፡ ለሌዋውያን ፡ ማገልገል ፡ ሊሆን ፡ በካህኑ ፤ በአሮን ፡ ልጅ ፡ በኢታማር ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ተቈጠረው ፡ የማደሪያው ፥ የምስክሩ ፡ ማደሪያ ፥ ዕቃ ፡ ድምር ፡ ይህ ፡ ነው ። ፳፪ ከይሁዳ ፡ ነገድም ፡ የሆነ ፡ የሆር ፡ የልጅ ፡ ልጅ ፥ የኡሪ ፡ ልጅ ፡ ባስልኤል ፡ እግዚአብሔር ፡ በሙሴ ፡ ፳፫ ያዘዘውን ፡ ሁሉ ፡ አደረገ ። ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ከዳን ፡ ነገድ ፡ የሆነ ፡ የአሂሳሚክ ፡ ልጅ ፡ ኤልያብ ፡ ነበረ ፤ እርሱም ፡ የቅርጽ ፡ ሠራተኛና ፡ ብልህ ፡ ሠራተኛ ፥ በሰማያዊ ፡ በሐምራዊም ፡ በቀይም ፡ ግምጃ ፥ በጥሩም ፡ በፍታ ፡ የሚሠራ ፡ ጠላፊ ፡ ነበረ ።

፳፬ የተሰጠው ፡ ወርቅ ፡ ሁሉ ፥ በመቅደሱ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ የተደረገው ፡ ወርቅ ፥ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ ሀያ ፡ ዘጠኝ ፡ መክሊት ፡ ሰባት ፡ ፳፭ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡ ነበረ ። በማኅበሩም ፡ ከሚቈጠሩት ፡ የተገኘ ፡ ብር ፥ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፥ መቶ ፡ መክሊትና ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ ሰባት ፡ ፳፮ መቶ ፡ ከሰባ ፡ አምስት ፡ ሰቅል ፡ ነበረ ። እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ የሰቅል ፡ ግማሽ ፡ ከተቈጠረው ፡ ከእያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ የተሰጠ ፡ ነው ፤ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ የተቈጠሩት ፡ ሁሉ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ። ፳፯ መቶውም ፡ የብር ፡ መክሊት ፡ የመቅደሱንና ፡ የመጋረጃውን ፡ እግሮች ፡ ለመሥራት ፡ ነበረ ፤ ከመቶውም ፡ መክሊት ፡ መቶ ፡ እግሮች ፡ አደረገ ፤ ለአንድ ፡ እግርም ፡ አንድ ፡ መክሊት ፡ ፳፰ ነበረ ። ከሺህ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡ አምስት ፡ ሰቅል ፡ የምሰሶቹን ፡ ኩላቦችና ፡ ዘንጎች ፡ አደረገ ፥ ፳፱ የምሰሶቹንም ፡ ጕልላቶች ፡ ለበጠ ። የተሰጠውም ፡ ናስ ፡ ሰባ ፡ መክሊትና ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ፴ አራት ፡ መቶ ፡ ሰቅል ፡ ነበረ ። ከእርሱም ፡ የመገናኛውን ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ እግሮች ፥ የናሱንም ፡ መሠዊያ ፥ በእርሱም ፡ የሆነውን ፡ የናሱን ፡ መከታ ፥ የመሠዊያውንም ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፥ ፴፩ በአደባባዩ ፡ ዙሪያ ፡ ያሉትን ፡ እግሮች ፥ የአደባባዩንም ፡ ደጃፍ ፡ እግሮች ፥ የማደሪያውንም ፡ ካስማዎች ፡ ሁሉ ፡ በአደባባዩ ፡ ዙሪያም ፡ ያሉትን ፡ ካስማዎች ፡ ሁሉ ፡ አደረገ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፱ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፥ በመቅደሱ ፡ ለማገልገል ፡ ከሰማያዊ ፡ ከሐምራዊም ፡ ከቀይ ፡ ግምጃም ፡ በብልሃት ፡ የተሠራ ፡ ልብስ ፥ ለአሮንም ፡ የተቀደሰውን ፡ ልብስ ፡ አደረጉ ።

፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፥ ኤፉዱን ፡ ከወርቅ ፡ ከሰማያዊም ፡ ከሐምራዊም ፡ ከቀይ ፡ ግምጃም ፡ ከተፈተለም ፡ ከጥሩ ፡ በፍታ ፡ ፫ አደረገ ። ወርቁንም ፡ ቀጥቅጠው ፡ እንደ ፡ ቅጠል ፡ ስስ ፡ አድርገው ፡ እንደ ፡ ፈትል ፡ ቈረጡ ። ብልህ ፡ ሠራተኛም ፡ እንደሚሠራ ፡ ሰማያዊ ፡ ሐምራዊም ፡ ቀይም ፡ ግምጃ ፡ የተፈተለም ፡ ጥሩ ፡ በፍታ ፡ ከእርሱ ፡ ጠለፉ ። ፬ ሁለቱ ፡ ወገን ፡ እንዲጋጠም ፡ በሁለቱ ፡ ጫንቃዎች ፡ ፭ ላይ ፡ የሚጋጠም ፡ ልብስ ፡ አደረጉት ። በላዩም ፡ መታጠቂያ ፡ ሆኖ ፡ በብልሃት ፡ የተጠለፈው ፡ የኤፉዱ ፡ ቋድ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ነበረ ፤ ከወርቅና ፡ ከሰማያዊ ፡ ከሐምራዊ ፡ ከቀይ ፡ ግምጃም ፡ ከተፈተለም ፡ ከጥሩ ፡ በፍታ ፡ የተሠራ ፡ ነበረ ።

፮ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፥ በወርቅ ፡ ፈርጥ ፡ የተያዙ ፡ የመረግድ ፡ ድንጋዮች ፡ ሠርተው ፡ እንደ ፡ ማኅተም ፡ ቅርጽ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ስም ፡ ቀረጹባቸው ። ፯ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የመታሰቢያ ፡ ድንጋዮች ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ በኤፉዱ ፡ ጫንቃዎች ፡ ላይ ፡ አደረጋቸው ።

፰ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፥ የደረቱን ፡ ኪስ ፡ ብልህ ፡ ሠራተኛ ፡ እንደሚሠራ ፡ እንደ ፡ ኤፉዱ ፡ አሠራር ፡ ከወርቅና ፡ ከሰማያዊ ፡ ከሐምራዊም ፡ ከቀይም ፡ ግምጃ ፡ ከተፈተለም ፡ ከጥሩ ፡ በፍታ ፡ አደረገው ። ፱ አራት ፡ ማዕዘንም ፡ ነበረ ፤ የደረቱን ፡ ኪስም ፡ ድርብ ፡ አደረጉ ፤ ርዝመቱ ፡ ስንዝር ፥ ወርዱም ፡ ስንዝር ፥ ድርብም ፡ ነበረ ። ፲ ስንቀኍዎቹንም ፡ በአራት ፡ ተራ ፡ አደረጉበት ፤ በፊተኛውም ፡ ተራ ፡ ሰርድዮን ፥ ቶጳዝዮን ፥ የሚያብረቀርቅ ፡ ዕንቍ ፤ ፲፩ በሁለተኛውም ፡ ተራ ፡ በሉር ፥ ሰንፔር ፥ አልማዝ ፤ ፲፪ በሦስተኛውም ፡ ተራ ፡ ያክንት ፥ ኬልቄዶን ፥ ፲፫ አሜቴስጢኖስ ፤ በአራተኛውም ፡ ተራ ፡ ቢረሌ ፥ መረግድ ፥ ኢያስጲድ ፡ በወርቅ ፡ ፈርጥ ፡ ተደረጉ ። ፲፬ የዕንቍዎችም ፡ ድንጋዮች ፡ እንደ ፡ አሥራ ፡ ሁለቱ ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ ልጆች ፡ ስሞች ፡ ነበሩ ፤ በየስማቸውም ፡ ማኅተሚያ ፡ እንደሚቀረጽ ፡ ተቀረጹ ፥ ስለ ፡ አሥራ ፡ ሁለቱም ፡ ነገዶች ፡ ነበሩ ። ፲፭ ለደረቱ ፡ ኪስም ፡ የተጐነጐኑትን ፡ ድሪዎች ፡ እንደ ፡ ገመድ ፡ አድርገው ፡ ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ፲፮ ሠሩ ። ሁለትም ፡ የወርቅ ፡ ፈርጦች ፥ ሁለትም ፡ የወርቅ ፡ ቀለበቶች ፡ ሠሩ ፤ ሁለቱንም ፡ ቀለበቶች ፡ በደረቱ ፡ ኪስ ፡ በሁለቱ ፡ ወገን ፡ ፲፯ አደረጉ ። ሁለቱንም ፡ የተጐነጐኑትን ፡ የወርቅ ፡ ድሪዎች ፡ በደረቱ ፡ ኪስ ፡ ወገኖች ፡ ወዳሉት ፡ ወደ ፡ ሁለቱ ፡ ቀለበቶች ፡ አገቡ ። ፲፰ የሁ

ለቱንም ፡ ድሪዎች ፡ ጫፎች ፡ በሁለቱ ፡ ፈር
ጦች ፡ ውስጥ ፡ አግብተው ፡ በኤፉዱ ፡ ጫንቃ
፲፱፤ ዎች ፡ ላይ ፡ በፊታቸው ፡ አደረጉ ። ሁለቱንም ፡
የወርቅ ፡ ቀለበቶች ፡ ሠሩ ፥ እነርሱንም ፡ በኤ
ፉዱ ፡ ፊት ፡ ስፌት ፡ በሰው ፡ በደረቱ ፡ ኪስ ፡ በሁ
፳፤ ለት ፡ ጫፎቹ ፡ ላይ ፡ አደረጉአቸው ። ደግሞም ፡
ሁለት ፡ የወርቅ ፡ ቀለበቶች ፡ ሠሩ ፥ በኤፉዱም ፡
ፊት ፥ ከጫንቃዎች ፡ በታች ፥ በብልሃት ፡ ከተ
ጠለፈ ፡ ከኤፉዱ ፡ ቋድ ፡ በላይ ፥ በመያዣው ፡
፳፩፤ አጠገብ ፡ አደረጉአቸው ። የደረቱ ፡ ኪስ ፡ በብ
ልሃት ፡ ከተጠለፈው ፡ ከኤፉዱ ፡ ቋድ ፡ በላይ ፡
እንዲሆን ፥ ከኤፉዱም ፡ እንዳይለይ ፡ የደረቱን ፡
ኪስ ፡ ከቀለበቶቹ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ኤፉዱ ፡ ቀለበ
ቶች ፡ በሰማያዊ ፡ ፈትል ፡ አሰሩት ።
፳፪፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፥ የኤ
ፉዱን ፡ ቀሚስ ፡ ሞላውን ፡ በሸማኔ ፡ ሥራ ፡ ሰማ
፳፫፤ ያዊ ፡ አደረገው ። በቀሚሱም ፡ መካከል ፡ አን
ገትጌ ፡ ነበረ ፤ እንዳይቀደድም ፡ እንደ ፡ ጥሩር ፡
የተሠራ ፡ ጥልፍ ፡ በአንገትጌው ፡ ዙሪያ ፡ ነበረ ።
፳፬፤ በቀሚሱም ፡ ታችኛ ፡ ዘርፍ ፡ ከሰማያዊ ፡ ከሐ
ምራዊም ፡ ከቀይም ፡ ግምጃ ፥ ከተፈተለ ፡ በፍ
፳፭፤ ታም ፡ ሮማኖች ፡ አደረጉ ። ከጥሩ ፡ ወርቅም ፡
ሸክላዎችን ፡ ሠሩ ፥ ሸክላዎቹንም ፡ ከሮማ
ኖች ፡ መካከል ፡ በቀሚሱ ፡ ዘርፍ ፡ ዙሪያ ፡ አደ
፳፮፤ ረጉ ። በቀሚሱ ፡ ዘርፍ ፡ ዙሪያ ፡ ሸክላንና ፡
ሮማንን ፥ ሸክላንና ፡ ሮማንን ፡ ለማገልገል ፡
አደረጉ ።
፳፯፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፥
እንደ ፡ ሸማኔ ፡ ሥራ ፡ ከጥሩ ፡ በፍታ ፡ ለአሮንና ፡
፳፰፤ ለልጆቹ ፡ ሸሚዞችን ፥ ከጥሩ ፡ በፍታም ፡ መጠ
ምጠሚያውን ፥ ከጥሩ ፡ በፍታም ፡ መልካሞቹን ፡
ቆቦች ፥ ከተፈተለም ፡ ከጥሩ ፡ በፍታ ፡ የእግር ፡
፳፱፤ ሱሪዎችን ፥ ከተፈተለም ፡ ከጥሩ ፡ በፍታ ፥ ከሰ
ማያዊም ፡ ከሐምራዊም ፡ ከቀይም ፡ ግምጃ ፡ በጥ
ልፍ ፡ አሠራር ፡ የተሠራ ፡ መታጠቂያውን ፡ አደ
ረጉ ።
፴፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፥
ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ የተቀደሰውን ፡ የአክሊል ፡ ምል
ክት ፡ ሠሩ ፤ በእርሱም ፡ እንደ ፡ ማኅተም ፡
ቅርጽ ፡ አድርገው ፦ ቅድስና ፡ ለእግዚአብ
፴፩፤ ሔር ፡ የሚል ፡ ጻፉበት ። በመጠምጠሚያውም ፡
ላይ ፡ ያንጠለጥሉት ፡ ዘንድ ፡ ሰማያዊውን ፡
ፈትል ፡ አሰሩበት ።
፴፪፤ እንዲሁም ፡ የመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ የማደሪ
ያው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ተጨረሰ ። እግዚአብሔ
ርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ፡ የእስራኤል ፡
፴፫፤ ልጆች ፡ አደረጉ ፤ እንዲሁ ፡ አደረጉ ። ማደሪ
ያውንም ፥ ድንኳኑንም ፥ ዕቃውንም ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ ሙሴ ፡ አመጡ ፤ መያዣዎቹን ፥ ሰንቆቹን ፥
መወርወሪያዎቹን ፥ ምሰሶቹንም ፥ እግሮቹንም ፤
፴፬፤ ከቀይ ፡ ከአውራ ፡ በግ ፡ ቁርበትም ፡ የተሠራ ፡
መደረቢያ ፥ ከአቆስጣ ፡ ቁርበትም ፡ የተሠራ ፡
፴፭፤ መደረቢያ ፥ የሚሸፍነውንም ፡ መጋረጃ ፤ የምስ
ክሩንም ፡ ታቦት ፥ መሎጊያዎቹንም ፥ የስርየት ፡
መክደኛውንም ፤ ገበታውንም ፥ ዕቃውንም ፡ ፴፮፤
ሁሉ ፥ የገጹንም ፡ ኅብስት ፤ ጥሩውንም ፡ መቅ ፴፯፤
ረዝ ፥ መብራቶቹንም ፥ በተራ ፡ የሚሆኑትንም ፡
ቀንዲሎች ፥ ዕቃውንም ፡ ሁሉ ፥ የመብራቱ
ንም ፡ ዘይት ፤ የወርቁንም ፡ መሠዊያ ፥ የቅብ ፴፰፤
ዓቱንም ፡ ዘይት ፥ ጣፋጩንም ፡ ዕጣን ፥ የድን
ኳኑንም ፡ ደጃፍ ፡ መጋረጃ ፤ የናሱንም ፡ መሠ ፴፱፤
ዊያ ፥ የናሱንም ፡ መከታ ፥ መሎጊያዎቹንም ፥
ዕቃውንም ፡ ሁሉ ፥ የመታጠቢያውን ፡ ሰንም ፡
መቀመጫውንም ፤ የአደባባዩንም ፡ መጋረጆች ፥ ፵፤
ምሰሶቹንም ፥ እግሮቹንም ፥ የአደባባዩንም ፡
ደጃፍ ፡ መጋረጃ ፥ አውታሮቹንም ፥ ካስማዎቹ
ንም ፥ ለመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ለማደሪያው ፡ ማገ
ልገያ ፡ የሚሆኑን ፡ ዕቃዎች ፡ ሁሉ ፤ በመቅደስ ፡ ፵፩፤
ውስጥ ፡ ለማገልገል ፡ በብልሃት ፡ የተሠሩትን ፡
ልብሶች ፥ በክህነትም ፡ ያገለግሉበት ፡ ዘንድ ፡
የተቀደሱትን ፡ የካህኑን ፡ የአሮንን ፡ ልብሶች ፥
የልጆቹንም ፡ ልብሶች ፡ አመጡ ። እግዚአብሔር ፡ ፵፪፤
ሙሴን ፡ እንዳዘዘ ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ የእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ ሥራውን ፡ ሁሉ ፡ ሠሩ ። ሙሴም ፡ ፵፫፤
ሥራውን ፡ ሁሉ ፡ አየ ፥ እነሆም ፡ አድርገውት ፡
ነበር ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ እንዲሁ ፡
አድርገውት ፡ ነበር ፤ ሙሴም ፡ ባረካቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፵ ።

እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ሲል ፡ ፩፤
ተናገረው ፦ ከመጀመሪያው ፡ ወር ፡ በፊተኛው ፡ ፪፤
ቀን ፡ የመገናኛውን ፡ ድንኳን ፡ ማደሪያ ፡ ትተክ
ላለህ ። በእርሱም ፡ ውስጥ ፡ የምስክሩን ፡ ታቦት ፡ ፫፤
ታኖራለህ ፥ ታቦቱንም ፡ በመጋረጃ ፡ ትጋርዳ
ለህ ። ገበታውንም ፡ አግብተህ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ፬፤
የሚኖረውን ፡ ዕቃ ፡ ታሰናዳለህ ፤ መቅረዙንም ፡
አግብተህ ፡ ቀንዲሎቹን ፡ ትለኩሳለህ ። ለዕጣ ፭፤
ንም ፡ የሚሆነውን ፡ የወርቅ ፡ መሠዊያ ፡ በምስ
ክሩ ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ ታኖራለህ ፥ በማደሪያውም ፡
ደጃፍ ፡ ፊት ፡ መጋረጃውን ፡ ትጋርዳለህ ። ለሚ ፮፤
ቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆነውንም ፡ መሠዊያ ፡
በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ በማደሪያው ፡ ደጅ ፡ ፊት ፡
ታኖረዋለህ ። የመታጠቢያውን ፡ ሰንም ፡ በመ ፯፤
ገናኛው ፡ ድንኳንና ፡ በመሠዊያው ፡ መካከል ፡
አኑረህ ፡ ውኃ ፡ ትጨምርበታለህ ። በዙሪያ ፰፤
ውም ፡ አደባባዩን ፡ ትተክላለህ ፥ የአደባባዩ
ንም ፡ ደጃፍ ፡ መጋረጃ ፡ ትዘረጋለህ ። የቅብዓ ፱፤
ቱንም ፡ ዘይት ፡ ወስደህ ፡ ማደሪያውን ፡ በእር
ሱም ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ትቀባለህ ፥ እርሱንም ፡
ዕቃውንም ፡ ሁሉ ፡ ትቀድሳለህ ፤ ቅዱስም ፡ ይሆ
ናል ። ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆነው ፲፤
ንም ፡ መሠዊያ ፡ ዕቃውንም ፡ ሁሉ ፡ ትቀባዋለህ ፥
መሠዊያውንም ፡ ትቀድሳለህ ፤ መሠዊያውም ፡
ቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፡ ይሆናል ። የመታጠቢያውን ፡ ፲፩፤
ሰንና ፡ መቀመጫውን ፡ ቀብተህ ፡ ትቀድሳለህ ።
አሮንንና ፡ ልጆቹንም ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድን ፲፪፤
ኳን ፡ ደጃፍ ፡ አቅርበህ ፡ በውኃ ፡ታጥባቸዋለህ ።
የተቀደሰውንም ፡ ልብስ ፡ አሮንን ፡ ታለብሰዋ ፲፫፤

ስህ ፤ በክህነትም ፡ ያገለግለኝ ፡ ዘንድ ፡ ቀብተህ ፡ ፲፬ ትቀድሰዋለህ = ልጆቹንም ፡ አቅርበህ ፡ ሸሚ ፲፭ ዞችን ፡ ታለብሳቸዋለህ ፤ በክህነትም ፡ ያገለግ ሉኝ ፡ ዘንድ ፡ አባታቸውን ፡ እንደ ፡ ቀባህ ፡ ትቀ ባቸዋለህ ፤ መቀባታቸውም ፡ ለልጅ ፡ ልጃቸው ፡ ፲፮ ለዘላለም ፡ ክህነት ፡ ይሆንላቸዋል = ሙሴም ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ =

፲፯ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ በፊ ተኛው ፡ ወር ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ማደሪ ፲፰ ያው ፡ ተተከለ = እግዚአብሔርም ፡ እንዳዘ ዘው ፡ ሙሴ ፡ ማደሪያውን ፡ ተከለ ፥ እግሮቹንም ፡ አኖረ ፥ ሳንቆቹንም ፡ አቆመ ፥ መወርወሪያዎ ቹንም ፡ አደረገባቸው ፥ ምሰሶቹንም ፡ አቆመ = ፲፱ ድንኳኑንም ፡ በማደሪያው ፡ ላይ ፡ ዘረጋ ፥ የድን ኳኑን ፡ መደረቢያ ፡ በላዩ ፡ አደረገበት =

፳ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ ጽላ ቱን ፡ ወስዶ ፡ በታቦቱ ፡ ውስጥ ፡ አኖረው ፥ መሎ ጊያዎቹን ፡ በታቦቱ ፡ ዘንድ ፡ አደረገ ፥ የስርየት ፡ መክደኛውንም ፡ በታቦቱ ፡ ላይ ፡ አኖረው ፤ ፳፩ ታቦቱን ፡ ወደ ፡ ማደሪያው ፡ አገባ ፥ የሚሸፍነ ውንም ፡ መጋረጃ ፡ አድርጎ ፡ የምስክሩን ፡ ታቦት ፡ ሸፈነ =

፳፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ ገበ ታውን ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፥ ከመጋ ረጃው ፡ ውጭ ፥ በማደሪያው ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ፳፫ አኖረው ፤ እንጀራውን ፡ በላዩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አሰናዳ =

፳፬ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ መቅ ረዙን ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፥ በገበ ታው ፡ ፊት ፡ ለፊት ፥ በማደሪያው ፡ በደቡብ ፡ ፳፭ በኩል ፡ አኖረ ፤ ቀንዲሎቹን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለኰሰ =

፳፮ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ የወር ቁን ፡ መሠዊያ ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ፳፯ በመጋረጃው ፡ ፊት ፡ አኖረ ፤ የጣፋጩን ፡ሽቱ ፡ ዕጣን ፡ ዐጠነበት =

፳፰ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ በማ ደሪያው ፡ ደጃፍ ፡ ፊት ፡ መጋረጃውን ፡ ዘረጋ = ፳፱ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆነውን ፡ መሠ ዊያ ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ በማደሪያው ፡ ደጅ ፡ ፊት ፡ አኖረ ፥ የሚቃጠለውንና ፡ የእህ ሉን ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዋበት =

፴ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ የመ ታጠቢያውን ፡ ሰን ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳንና ፡ በመሠዊያው ፡ መካከል ፡ አኖረ ፥ ለመታጠቢ ፴፩ ያም ፡ ውኃን ፡ ጨመረበት = በእርሱም ፡ ሙሴና ፡ አሮን ፡ ልጆቹም ፡ እጆቻቸውንና ፡ እግሮቻቸ ፴፪ ውን ፡ ታጠቡ ፤ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፥ ወደ ፡ መሠዊያውም ፡ በቀረቡ ፡ ጊዜ ፡ ይታጠቡ ፡ ነበር =

፴፫ በማደሪያውና ፡ በመሠዊያውም ፡ ዙሪያ ፡ አደ ባባዩን ፡ ተከለ ፤ የአደባባዩንም ፡ ደጃፍ ፡ መጋ ረጃ ፡ ዘረጋ = እንዲሁም ፡ ሙሴ ፡ ሥራውን ፡ ፈጸመ =

፴፬ ደመናውም ፡ የመገናኛውን ፡ ድንኳን ፡ ከደነ ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ ማደሪያውን ፡ሞላ = ፴፭ ደመናውም ፡ በላዩ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ የእግዚአብሔ ርም ፡ ክብር ፡ ማደሪያውን ፡ ስለ ፡ ሞላ ፡ ሙሴ ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ይገባ ፡ ዘንድ ፡ አል ፴፮ ቻለም = ደመናውም ፡ ከማደሪያው ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በመንገዳቸው ፡ ፴፯ ሁሉ ፡ ይጓዙ ፡ ነበር = ደመናው ፡ ባይነሣ ፡ እስ ከሚነሣበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ አይጓዙም ፡ ነበር = ፴፰ በመንገዳቸውም ፡ ሁሉ ፡ በእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ደመና ፡ በማደሪ ያው ፡ ላይ ፡ በቀን ፡ ነበረና ፥ እሳትም ፡ በሌሊት ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ ነበረና =

# ኦሪት ፡ ዘሌዋውያን ፨

ምዕራፍ ፡ ፩ =

፩ እግዚአብሔርም ፡ ከመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ሙሴን ፡ ጠርቶ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ተና ፪ ገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— ከእናንተ ፡ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መባ ፡ ሲያቀርብ ፡ መባችሁን ፡ ከእንስሳ ፡ ወገን ፡ ከላሞች ፡ ወይም ፡ ከበጎች ፡ ታቀርባላችሁ =

፫ መባውም ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ከላ ሞች ፡ መንጋ ፡ ቢሆን ፥ ነውር ፡ የሌለበትን ፡ ተባቱን ፡ ያቀርባል ፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንዲሠምር ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ፬ ፊት ፡ ያቀርበዋል = እጁንም ፡ በሚቃጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይጭናል ፤ ያስተሰርይ ለትም ፡ ዘንድ ፡ የሠመረ ፡ ይሆንለታል = ፭ በሬ ውንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያርደዋል ፤ የአ ሮንም ፡ ልጆች ፡ ካህናት ፡ ደሙን ፡ ያቀርባሉ ፤ ደሙንም ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ፊት ፡ ባለው ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ በዙሪያው ፡ ይረ ፮ ጩታል = የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ ፯ ይገፍፈዋል ፥ በየብልቱም ፡ ይቈርጠዋል = የካ ህኑም ፡ የአሮን ፡ ልጆች ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ እሳት ፡ ያነድዳሉ ፥ በእሳቱም ፡ ላይ ፡ እንጨት ፡ ፰ ይደረድራሉ ፤ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ካህናቱ ፡ የተቈረጡትን ፡ ብልቶች ፡ ራሱንም ፡ ስቡንም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ በእሳቱ ፡ ላይ ፡ ባለው ፡ በእንጨቱ ፡ ላይ ፡ ይረበርቡታል ፤ ፱ የሆድ ፡ ዕቃ ውንና ፡ እግሮቹን ፡ ግን ፡ በውኃ ፡ ያጥባል ፤ ካህኑም ፡ ሁሉን ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡

ለህ ፤ በክህነትም ፡ ያገለግለኝ ፡ ዘንድ ፡ ቀብተህ ፡ ትቀድሰዋለህ ፡፡ ፲፬ ልጆቹንም ፡ አቅርበህ ፡ ሸሚዞችን ፡ ታለብሳቸዋለህ ፤ ፲፭ በክህነትም ፡ ያገለግሉኝ ፡ ዘንድ ፡ አባታቸውን ፡ እንደ ፡ ቀባህ ፡ ትቀባቸዋለህ ፤ መቀባታቸውም ፡ ለልጅ ፡ ልጃቸው ፡ ለዘላለም ፡ ክህነት ፡ ይሆንላቸዋል ፡፡ ፲፮ ሙሴም ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ፡፡

፲፯ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ በፊተኛው ፡ ወር ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ማደሪያው ፡ ተተከለ ፡፡ ፲፰ እግዚአብሔርም ፡ እንዳዘዘው ፡ ሙሴ ፡ ማደሪያውን ፡ ተከለ ፥ እግሮቹንም ፡ አኖረ ፥ ሳንቆቹንም ፡ አቆመ ፥ መወርወሪያዎቹንም ፡ አደረገባቸው ፥ ምሰሶቹንም ፡ አቆመ ፡፡ ፲፱ ድንኳኑንም ፡ በማደሪያው ፡ ላይ ፡ ዘረጋ ፥ የድንኳኑን ፡ መደረቢያ ፡ በላዩ ፡ አደረገበት ፡፡

፳ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ ጽላቱን ፡ ወስዶ ፡ በታቦቱ ፡ ውስጥ ፡ አኖረው ፥ መሎጊያዎቹን ፡ በታቦቱ ፡ ዘንድ ፡ አደረገ ፥ የስርየት ፡ መክደኛውንም ፡ በታቦቱ ፡ ላይ ፡ አኖረው ፤ ፳፩ ታቦቱን ፡ ወደ ፡ ማደሪያው ፡ አገባ ፥ የሚሸፍነውንም ፡ መጋረጃ ፡ አድርጎ ፡ የምስክሩን ፡ ታቦት ፡ ሸፈነ ፡፡

፳፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ ገበታውን ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፥ ከመጋረጃው ፡ ውጭ ፥ በማደሪያው ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ አኖረው ፤ ፳፫ እንጀራውን ፡ በላዩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አሰናዳ ፡፡

፳፬ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ መቅረዙን ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፥ በገበታው ፡ ፊት ፡ ለፊት ፥ በማደሪያው ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ አኖረ ፤ ፳፭ ቀንዲሎቹን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለኰሰ ፡፡

፳፮ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ የወርቁን ፡ መሠዊያ ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ በመጋረጃው ፡ ፊት ፡ አኖረ ፤ ፳፯ የጣፋጩን ፡ ሽቱ ፡ ዕጣን ፡ ዐጠነበት ፡፡

፳፰ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ በማደሪያው ፡ ደጃፍ ፡ ፊት ፡ መጋረጃውን ፡ ዘረጋ ፡፡ ፳፱ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆነውን ፡ መሠዊያ ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ በማደሪያው ፡ ደጅ ፡ ፊት ፡ አኖረ ፥ የሚቃጠለውንና ፡ የእህሉን ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዋበት ፡፡

፴ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ የመታጠቢያውን ፡ ሰን ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳንና ፡ በመሠዊያው ፡ መካከል ፡ አኖረ ፥ ለመታጠቢያም ፡ ውኃ ፡ ጨመረበት ፡፡ ፴፩ በእርሱም ፡ ሙሴና ፡ አሮን ፡ ልጆቹም ፡ እጆቻቸውንና ፡ እግሮቻቸውን ፡ ታጠቡ ፤ ፴፪ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፥ ወደ ፡ መሠዊያውም ፡ በቀረቡ ፡ ጊዜ ፡ ይታጠቡ ፡ ነበር ፡፡

፴፫ በማደሪያውና ፡ በመሠዊያውም ፡ ዙሪያ ፡ አደባባዩን ፡ ተከለ ፤ የአደባባዩንም ፡ ደጃፍ ፡ መጋረጃ ፡ ዘረጋ ፡፡ እንዲሁም ፡ ሙሴ ፡ ሥራውን ፡ ፈጸመ ፡፡

፴፬ ደመናውም ፡ የመገናኛውን ፡ ድንኳን ፡ ከደነ ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ ማደሪያውን ፡ ሞላ ፡፡ ፴፭ ደመናውም ፡ በላዩ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ ማደሪያውን ፡ ስለ ፡ ሞላ ፡ ሙሴ ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ይገባ ፡ ዘንድ ፡ አልቻለም ፡፡ ፴፮ ደመናውም ፡ ከማደሪያው ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በመንገዳቸው ፡ ሁሉ ፡ ይጓዙ ፡ ነበር ፡፡ ፴፯ ደመናው ፡ ባይነሣ ፡ እስከሚነሣበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ አይጓዙም ፡ ነበር ፡፡ ፴፰ በመንገዳቸውም ፡ ሁሉ ፡ በእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ደመና ፡ በማደሪያው ፡ ላይ ፡ በቀን ፡ ነበረና ፥ እሳትም ፡ በሌሊት ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ ነበረና ፡፡

# ኦሪት ፡ ዘሌዋውያን ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፩ ፡፡

፩ እግዚአብሔርም ፡ ከመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ሙሴን ፡ ጠርቶ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ተናገረው ፡— ፪ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— ከእናንተ ፡ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መባ ፡ ሲያቀርብ ፡ መባችሁን ፡ ከእንስሳ ፡ ወገን ፡ ከላሞች ፡ ወይም ፡ ከበጎች ፡ ታቀርባላችሁ ፡፡

፫ መባውም ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ከላሞች ፡ መንጋ ፡ ቢሆን ፥ ነውር ፡ የሌለበትን ፡ ተባቱን ፡ ያቀርባል ፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንዲሠምር ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ፊት ፡ ያቀርበዋል ፡፡ ፬ እጁንም ፡ በሚቃጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይጭናል ፤ ያስተሰርይለትም ፡ ዘንድ ፡ የሠመረ ፡ ይሆንለታል ፡፡ ፭ በሬውንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያርደዋል ፤ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ካህናቱ ፡ ደሙን ፡ ያቀርባሉ ፤ ደሙንም ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ፊት ፡ ባለው ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ በዙሪያው ፡ ይረጩታል ፡፡ ፮ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ ይገፍፈዋል ፥ በየብልቱም ፡ ይቈርጠዋል ፡፡ ፯ የካህኑም ፡ የአሮን ፡ ልጆች ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ እሳት ፡ ያነድዳሉ ፥ በእሳቱም ፡ ላይ ፡ እንጨት ፡ ይደረድራሉ ፤ ፰ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ካህናቱ ፡ የተቈረጡትን ፡ ብልቶች ፡ ራሱንም ፡ ስቡንም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ በእሳቱ ፡ ላይ ፡ ባለው ፡ በእንጨቱ ፡ ላይ ፡ ይረበርቡታል ፤ ፱ የሆድ ፡ ዕቃውንና ፡ እግሮቹን ፡ ግን ፡ በውኃ ፡ ያጥባል ፤ ካህኑም ፡ ሁሉን ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡

የእሳት ፡ ቍርባን ፡ አድርጎ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ።

፲ ቍርባኑም ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ከበጎች ፡ ወይም ፡ ከፍየሎች ፡ ቢሆን ÷ ነውር ፡ የሌለበትን ፡ ተባቱን ፡ ያቀርበዋል ። ፲፩ በመሠዊያው ፡ አጠገብ ፡ በሰሜን ፡ ወገን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያርደዋል ፤ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ካህናቱ ፡ ደሙን ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ በዙሪያው ፡ ይረጩታል ። ፲፪ በየብልቱም ፡ ራሱንም ፡ ስቡንም ፡ ይቈርጠዋል ፤ ካህኑም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ በእሳቱ ፡ ላይ ፡ ባለው ፡ በእንጨቱ ፡ ላይ ፡ ይረበርበዋል ፤ ፲፫ የሆድ ፡ ዕቃውንና ፡ እግሮቹን ፡ ግን ፡ በውኃ ፡ ያጥባል ። ካህኑም ፡ ሁሉን ፡ አቅርቦ ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ፤ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ ነው ።

፲፬ ለእግዚአብሔርም ፡ የሚቀርበው ፡ ቍርባን ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ከወፎች ፡ ቢሆን ÷ ቍርባኑን ፡ ከዋኖስ ፡ ወይም ፡ ከርግብ ፡ ያቀርባል ። ፲፭ ካህኑም ፡ ወደ ፡ መሠዊያው ፡ ያቀርበዋል ÷ ራሱንም ፡ ይቈለምመዋል ÷ በመሠዊያውም ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ። ደሙም ፡ በመሠዊያው ፡ አጠገብ ፡ ይንጠፈጠፋል ፤ ፲፮ የሆድ ፡ ዕቃውንም ፡ ከላባዎች ፡ ጋር ፡ ለይቶ ፡ በመሠዊያው ፡ አጠገብ ፡ በምሥራቅ ፡ ወገን ፡ በአመዱ ፡ ስፍራ ፡ ይጥለዋል ፤ ፲፯ በክንፎቹም ፡ ይቀድደዋል ÷ ነገር ፡ ግን ፡ አይከፍለውም ። ካህኑም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ በእሳቱ ፡ ላይ ፡ ባለው ፡ በእንጨቱ ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ፤ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሲያቀርብ ፡ ቍርባኑ ፡ ከመልካም ፡ ዱቄት ፡ ይሁን ፤ ዘይትም ፡ ያፈስስበታል ÷ ዕጣንም ፡ ይጨምርበታል ፤ ፪ ወደ ፡ አሮንም ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ካህናቱ ፡ ያመጣዋል ፤ ከመልካም ፡ ዱቄቱና ፡ ከዘይቱም ፡ አንድ ፡ እፍኝ ፡ ሙሉና ፡ ዕጣኑን ፡ ሁሉ ፡ ወስዶ ፡ ካህኑ ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ ለመታሰቢያ ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ። ፫ ከእህሉም ፡ ቍርባን ፡ የተረፈው ፡ ለአሮንና ፡ ለልጆቹ ፡ ይሆናል ፤ ይህም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚሆን ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱሳን ፡ ነው ።

፬ በእቶን ፡ የተጋገረውን ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ስታቀርብ ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ የመልካም ፡ ዱቄት ፡ የቂጣ ፡ እንጎቻ ፡ ወይም ፡ በዘይት ፡ የተቀባ ፡ ስስ ፡ ቂጣ ፡ ይሁን ። ፭ ቍርባንህም ፡ በምጣድ ፡ የተጋገረ ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ቢሆን ÷ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ የመልካም ፡ ዱቄት ፡ ቂጣ ፡ ይሁን ። ፮ ቈርሰህም ፡ ዘይት ፡ ታፈስስበታለህ ፤ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ነው ። ፯ ቍርባንህም ፡ በመቀቀያ ፡ የበሰለ ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ቢሆን ÷ ዘይት ፡ የገባበት ፡ ከመልካም ፡ ዱቄት ፡ የተደረገ ፡ ይሁን ። ፰ ከዚህም ፡ የተደረገውን ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ታመጣለህ ፤ ለካህኑም ፡ ይሰጣል ÷ እርሱም ፡ ወደ ፡ መሠዊያው ፡ ያቀርበዋል ። ፱ ካህኑም ፡ ከእህሉ ፡ ቍርባን ፡ መታሰቢያውን ፡ አንሥቶ ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ። ፲ ከእህሉም ፡ ቍርባን ፡ የተረፈው ፡ ለአሮንና ፡ ለልጆቹ ፡ ይሆናል ፤ ይህም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚሆን ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱሳን ፡ ነው ።

፲፩ እርሾ ፡ ያለበት ፡ ነገር ፡ ማርም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ አታቀርቡምና ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የምታቀርቡት ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ሁሉ ፡ እርሾ ፡ አይሁንበት ። ፲፪ እነዚህንም ፡ የበኵራት ፡ ቍርባን ፡ አድርጋችሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ታቀርባላችሁ ፤ እንደ ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ ግን ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ አይቃጠሉም ። ፲፫ የምታቀርበውን ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ሁሉ ፡ በጨው ፡ ታጣፍጠዋለህ ፤ የአምላክህንም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ጨው ፡ ከእህል ፡ ቍርባንህ ፡ አታጕድልም ፤ በቍርባንህ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ጨው ፡ ታቀርባለህ ።

፲፬ ከበኵራትም ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ብታቀርብ ፡ ስለዚህ ፡ ቍርባን ፡ በእሳት ፡ የተጠበሰና ፡ የተፈተገ ፡ የእህል ፡ እሸት ፡ ታቀርባለህ ። ፲፭ ዘይትም ፡ ታፈስስበታለህ ÷ ዕጣንም ፡ ትጨምርበታለህ ፤ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ነው ። ፲፮ ካህኑም ፡ ከተፈተገው ፡ እህል ፡ ከዘይቱም ፡ ወስዶ ፡ ከዕጣኑ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ መታሰቢያውን ፡ ያቃጥላል ፤ ይህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ቍርባኑም ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ ቢሆን ÷ ከላሞች ፡ መንጋ ፡ ተባት ፡ ወይም ፡ እንስት ፡ ቢያቀርብ ÷ ነውር ፡ የሌለበትን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያቅርብ ። ፪ እጁንም ፡ በቍርባኑ ፡ በቀረበው ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይጭናል ÷ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ አጠገብ ፡ ያርደዋል ፤ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ካህናቱ ፡ ደሙን ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ በዙሪያው ፡ ይረጩታል ። ፫ ከደኅንነቱም ፡ መሥዋዕት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ አድርጎ ፡ ያቀርባል ፤ የሆድ ፡ ዕቃውን ፡ የሚሸፍነውን ፡ ስብ ÷ በሆድ ፡ ዕቃውም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ስብ ፡ ሁሉ ÷ ፬ ሁለቱንም ፡ ኵላሊቶች ÷ በእነርሱም ፡ ላይና ፡ በጎድኑ ፡ አጠገብ ፡ ያለውን ፡ ስብ ÷ በጕበቱም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ መረብ ፡ ከኵላሊቶች ፡ ጋር ፡ ይወስዳል ። ፭ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ከሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡

ጋር ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ በእሳቱ ፡ ላይ ፡ በለው ፡
በእንጨቱ ፡ ላይ ፡ ያቃጥሉታል ፤ የእሳት ፡ ቍር
ባን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ ነው ።
፮፤ ለእግዚአብሔርም ፡ ለደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡
የሚያቀርበው ፡ ቍርባኑ ፡ ከበጎች ፡ ተባት ፡
ወይም ፡ እንስት ፡ ቢሆን ፥ ነውር ፡ የሌለበትን ፡
፯፤ ያቀርባል ። ለቍርባኑ ፡ ጠቦትን ፡ ቢያቀርብ ፡
፰፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያቀርበዋል ፤ እጁንም ፡
ለቍርባን ፡ በቀረበው ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይጭናል ፥
በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ፊት ፡ ያርደዋል ፤ የአ
ሮንም ፡ ልጆች ፡ ደሙን ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡
፱፤ በዙሪያው ፡ ይረጩታል ። ከደኅንነቱም ፡ መሥ
ዋዕት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡
አድርጎ ፡ ያቀርባል ፤ ስቡን ፥ እስከ ፡ ጀርባውም ፡
ድረስ ፡ የተቈረጠ ፡ ላቱን ፡ ሁሉ ፥ የሆድ ፡ ዕቃ
ውንም ፡ የሚሸፍነውን ፡ ስብ ፥ በሆድ ፡ ዕቃ
፲፤ ውም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ስብ ፡ ሁሉ ፥ ሁለቱንም ፡
ኵላሊቶች ፥ በእነርሱም ፡ ላይና ፡ በጎድኑ ፡ አጠ
ገብ ፡ ያለውን ፡ ስብ ፥ በጕበቱም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡
፲፩፤ መረብ ፡ ከኵላሊቶች ፡ ጋር ፡ ይወስዳል ። ካህ
ኑም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ፤ በእ
ሳት ፡ ላይ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተደረገ ፡ የቍር
ባን ፡ መብል ፡ ነው ።
፲፪፤ ቍርባኑም ፡ ፍየል ፡ ቢሆን ፡ በእግዚአብሔር ፡
፲፫፤ ፊት ፡ ያቀርበዋል ፤ እጁንም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡
ይጭንበታል ፥ በመገናኛውም ፡ ድንኳን ፡ ፊት ፡
ያርደዋል ፤ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ደሙን ፡ በመ
፲፬፤ ሠዊያው ፡ ላይ ፡ በዙሪያው ፡ ይረጩታል ። ከእ
ርሱም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡
አድርጎ ፡ ያቀርበዋል ፤ ሆድ ፡ ዕቃውን ፡ የሚሸ
ፍነውን ፡ ስብ ፥ በሆድ ፡ ዕቃውም ፡ ላይ ፡ ያለ
፲፭፤ ውን ፡ ስብ ፡ ሁሉ ፥ ሁለቱንም ፡ ኵላሊቶች ፥
በእነርሱም ፡ ላይና ፡ በጎድኑ ፡ አጠገብ ፡ ያለውን ፡
ስብ ፥ በጕበቱም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ መረብ ፡ ከኵ
፲፮፤ ላሊቶች ፡ ጋር ፡ ይወስዳል ። ካህኑም ፡ በመሠዊ
ያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ፤ በእሳት ፡ ላይ ፡ ጣፋጭ ፡
ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ የተደረገ ፡ መብል ፡ ነው ። ስቡ ፡
፲፯፤ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ነው ። ስብና ፡ ደም ፡
እንዳትበሉ ፡ በምትኖሩበት ፡ ሁሉ ፡ ለልጅ ፡
ልጃችሁ ፡ የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ተና
፪፤ ገረው ፦ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡
ንገራቸው ፦ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ሳያውቅ ፡
ኃጢአት ፡ ቢሠራ ፥ እግዚአብሔርም ፦ አት
ሥሩ ፡ ካላቸው ፡ ትእዛዛት ፡ አንዲቱን ፡ ቢተላ
፫፤ ለፍ ፥ የተቀባውም ፡ ካህን ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡
በደል ፡ እንዲቈጠርባቸው ፡ ኃጢአት ፡ ቢሠራ ፥
ስለ ፡ ሠራው ፡ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ ነውር ፡ የሌለበት ፡
ወይፈን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለኃጢአት ፡ መሥ
፬፤ ዋዕት ፡ ያቀርበዋል ። ወይፈኑንም ፡ ወደ ፡ መገ
ናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ያመጣዋል ፤ እጁንም ፡ በወይፈኑ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡
ይጭነዋል ፥ ወይፈኑንም ፡ በእግዚአብሔር ፡
፭፤ ፊት ፡ ያርደዋል ። የተቀባውም ፡ ካህን ፡ ከወ
ይፈኑ ፡ ደም ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድን
፮፤ ኳን ፡ ያመጣዋል ፤ ካህኑም ፡ ጣቱን ፡ በደሙ ፡
ውስጥ ፡ ነክሮ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በመቅ
ደሱ ፡ መጋረጃ ፡ ፊት ፡ ደሙን ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡
፯፤ ይረጨዋል ። ካህኑም ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡
ውስጥ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያለው ፡ ጣፋጭ ፡
ዕጣን ፡ በሚታጠንበት ፡ መሠዊያ ፡ ቀንዶች ፡
ላይ ፡ ከደሙ ፡ ያደርጋል ፤ የተረፈውንም ፡
የወይፈኑን ፡ ደም ፡ ሁሉ ፡ በመገናኛው ፡ ድን
ኳን ፡ ደጅ ፡ ባለው ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋ
ዕት ፡ በሚሆነው ፡ መሠዊያ ፡ በታች ፡ ያፈስሰ
፰፤ ዋል ። ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ ከሚታረ
ደው ፡ ወይፈን ፡ ስብን ፡ ሁሉ ፡ ይወስዳል ፤ ሆድ ፡
ዕቃውን ፡ የሚሸፍነውን ፡ ስብ ፥ በሆድ ፡ ዕቃ
፱፤ ውም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ስብ ፡ ሁሉ ፥ ሁለቱንም ፡
ኵላሊቶች ፥ በእነርሱም ፡ ላይና ፡ በጎድኑ ፡ አጠ
ገብ ፡ ያለውን ፡ ስብ ፥ በጕበቱም ፡ ላይ ፡ ያለ
፲፤ ውን ፡ መረብ ፡ ከኵላሊቶች ፡ ጋር ፥ ለደኅንነት ፡
መሥዋዕት ፡ ከታረደው ፡ ወይፈን ፡ እንደ ፡ ተወ
ሰደው ፡ ይወስዳል ። ካህኑም ፡ ለሚቃጠል ፡
መሥዋዕት ፡ በሚሆነው ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ ያቃ
፲፩፤ ጥለዋል ። የወይፈኑን ፡ ቍርበት ፥ ሥጋው
ንም ፡ ሁሉ ፥ ራሱንም ፥ እግሮቹንም ፥ ሆድ ፡
፲፪፤ ዕቃውንም ፥ ፈርሱንም ፥ ወይፈኑን ፡ ሁሉ ፡
ከሰፈሩ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አመድ ፡ ወደሚፈስ
ስበት ፡ ወደ ፡ ንጹሕ ፡ ስፍራ ፡ ይወስደዋል ፥
በእንጨትም ፡ ላይ ፡ በእሳት ፡ ያቃጥለዋል ፤
አመድ ፡ በሚፈስስበት ፡ ስፍራ ፡ ይቃጠላል ።
፲፫፤ የእስራኤል ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ቢስቱ ፥ ነገ
ሩም ፡ ከጉባኤው ፡ ፊት ፡ ቢሸሸግ ፥ እግዚአብ
ሔርም ፦ አትሥሩ ፡ ካላቸው ፡ ትእዛዛት ፡ አን
፲፬፤ ዲቱን ፡ ቢተላለፉ ፥ እንዲህም ፡ ቢበድሉ ፥ የሠ
ሩት ፡ ኃጢአት ፡ ሲታወቅ ፡ ጉባኤው ፡ ስለ ፡
ኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ወይፈንን ፡ ያቀርባሉ ፤
ወደ ፡ መገናኛውም ፡ ድንኳን ፡ ፊት ፡ ያመጡ
፲፭፤ ታል ። የጉባኤውም ፡ ሽማግሌዎች ፡ እጆቻቸ
ውን ፡ በወይፈኑ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ይጭናሉ ፤ ወይፈኑም ፡ በእግዚአብሔር ፡
፲፮፤ ፊት ፡ ይታረዳል ። የተቀባውም ፡ ካህን ፡ ከወ
ይፈኑ ፡ ደም ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ያመ
፲፯፤ ጣል ፤ ካህኑም ፡ ጣቱን ፡ በደሙ ፡ ውስጥ ፡ ነክሮ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በመጋረጃው ፡ ፊት ፡
፲፰፤ ለፊት ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ይረጨዋል ። በመገና
ኛውም ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ባለው ፡ በዕጣን ፡ መሠዊያው ፡ ቀንዶች ፡
ላይ ፡ ከደሙ ፡ ያደርጋል ፤ ደሙንም ፡ ሁሉ ፡
በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጅ ፡ ባለው ፡ ለሚቃ
ጠል ፡ መሥዋዕት ፡ በሚሆነው ፡ መሠዊያ ፡
፲፱፤ በታች ፡ ያፈስሰዋል ። ስቡንም ፡ ሁሉ ፡ ከእ
ርሱ ፡ ወስዶ ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ።
፳፤ እንዲህም ፡ በወይፈኑ ፡ ያደርጋል ፤ ስለ ፡ ኃጢ
አት ፡ መሥዋዕት ፡ በታረደው ፡ ወይፈን ፡ እንዳ

ደረገ ፡ እንዲሁ ፡ በዚህ ፡ ያደርጋል ፤ ካህኑም ፡
ስለ ፡ እነርሱ ፡ ያስተሰርያል ÷ እነርሱም ፡ ይቅር ፡
፳፩ ፡ ይባላሉ ። ወይፈኑንም ፡ ከሰፈሩ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡
ይወስደዋል ÷ የፊተኛውንም ፡ ወይፈን ፡ እንዳ
ቃጠለ ፡ ያቃጥለዋል ፤ ይህ ፡ የማኅበሩ ፡ የኃጢ
አት ፡ መሥዋዕት ፡ ነው ።

፳፪ ፡ አንድ ፡ መኰንንም ፡ ኃጢአትን ፡ ሲሠራ ÷
ሳያውቅም ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላኩ ፡— አት
ሥራ ፡ ያለውን ፡ ትእዛዝ ፡ ሲተላለፍ ÷ እንዲ
፳፫ ፡ ህም ፡ ሲበድል ÷ የሠራው ፡ ኃጢአት ፡ ቢታ
ወቅ ÷ ነውር ፡ የሌለበትን ፡ ተባት ፡ ፍየል ፡ ለቍ
፳፬ ፡ ርባኑ ፡ ያቀርበዋል ፤ በፍየሉም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡
እጁን ፡ ይጭናል ፤ የሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡
በሚታረድበት ፡ ስፍራ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ያርደዋል ፤ እርሱ ፡ የኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡
፳፭ ፡ ነው ። ካህኑም ፡ ከኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ደም ፡
በጣቱ ፡ ወስዶ ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ በሚ
ሆነው ፡ መሠዊያ ፡ ቀንዶች ፡ ያደርገዋል ፤ የተ
ረፈውንም ፡ ደም ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡
ከሚሆነው ፡ መሠዊያ ፡ በታች ፡ ያፈስሰዋል ።
፳፮ ፡ ስቡንም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡
ስብ ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ። ካህ
ኑም ፡ ኃጢአቱን ፡ ያስተሰርይለታል ÷ እርሱም ፡
ይቅር ፡ ይባላል ።

፳፯ ፡ ከአገሩ ፡ ሕዝብም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ኃጢአ
ትን ፡ ሳያውቅ ፡ ቢሠራ ÷ እግዚአብሔርም ፡—
አትሥራ ፡ ያለውን ፡ ትእዛዝ ፡ ቢተላለፍ ÷ ቢበ
፳፰ ፡ ድልም ÷ ለእርሱም ፡ የሠራው ፡ ኃጢአት ፡
ቢታወቀው ÷ ስለ ፡ ሠራው ፡ ኃጢአት ፡ ነውር ፡
የሌለባትን ፡ እንስት ፡ ፍየል ፡ ለቍርባኑ ፡ ያመ
፳፱ ፡ ጣል ። እጁንም ፡ በኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡
ራስ ፡ ላይ ፡ ይጭናል ፤ የሚቃጠልም ፡ መሥ
ዋዕት ፡ በሚታረድበት ፡ ስፍራ ፡ የኃጢአትን ፡
፴ ፡ መሥዋዕት ፡ ያርዳል ። ካህኑም ፡ ከደምዋ ፡
በጣቱ ፡ ወስዶ ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ በሚ
ሆነው ፡ መሠዊያ ፡ ቀንዶች ፡ ላይ ፡ ያደርገዋል ÷
ደሙንም ፡ ሁሉ ፡ ከመሠዊያው ፡ በታች ፡ ያፈ
፴፩ ፡ ስሰዋል ። ስቡም ፡ ሁሉ ፡ ከደኅንነት ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ላይ ፡ እንደሚወሰድ ÷ ስብዋን ፡ ሁሉ ፡
ይወስዳል ፤ ካህኑም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡
ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለ
ዋል ፤ ካህኑም ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ያስተሰርያል ÷
እርሱም ፡ ይቅር ፡ ይባላል ።

፴፪ ፡ ስለ ፡ ኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ የበግ ፡ ጠቦት ፡
ቢያቀርብ ÷ ነውር ፡ የሌለባትን ፡ እንስት ፡ ያመ
፴፫ ፡ ጣል ። እጁንም ፡ በኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡
ራስ ፡ ላይ ፡ ይጭናል ÷ የሚቃጠልም ፡ መሥ
ዋዕት ፡ በሚታረድበት ፡ ስፍራ ፡ ለኃጢአት ፡
፴፬ ፡ መሥዋዕት ፡ ያርዳታል ። ካህኑም ፡ ከኃጢ
አት ፡ መሥዋዕት ፡ ደም ፡ በጣቱ ፡ ወስዶ ፡ ለሚ
ቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ በሚሆነው ፡ መሠዊያ ፡
ቀንዶች ፡ ላይ ፡ ያደርገዋል ÷ ደሙንም ፡ ሁሉ ፡
፴፭ ፡ ከመሠዊያው ፡ በታች ፡ ያፈስሰዋል ። ስቡ ፡
ሁሉ ፡ ለደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ ከታረደው ፡
ጠቦት ፡ ላይ ፡ እንደሚወሰድ ፡ ስብዋን ፡ ይወስ
ዳል ፤ ካህኑም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በእሳት ፡
በተቃጠለው ፡ ቍርባን ፡ ላይ ፡ በመሠዊያው ፡
ላይ ፡ ያቃጥለዋል ። ካህኑም ፡ ስለ ፡ ሠራው ፡
ኃጢአት ፡ ያስተሰርይለታል ÷ እርሱም ፡ ይቅር ፡
ይባላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ የሚያምለውን ፡ ቃል ፡ ቢሰማ ÷
ምስክር ፡ ሆኖም ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ አይቶ ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ ወይም ፡ አውቆ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ባይናገር ÷
ኃጢአት ፡ መሥራቱ ፡ ነውና ፡ በደሉን ፡ ይሸከ
፪ ፡ ማል ። ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ሳይታወቀው ፡
ርኩስ ፡ ነገር ፡ ቢነካ ÷ የረከሰም ፡ አውሬ ፡ በድን ÷
ወይም ፡ የረከሰ ፡ ከብት ፡ በድን ÷ ወይም ፡ የረ
ከሰ ፡ የተንቀሳቀሰ ፡ እንስሳ ፡ በድን ፡ ቢሆን ÷
እርሱም ፡ ርኩስ ፡ ቢሆን ፡ ነገሩ ፡ በታወቀው ፡
፫ ፡ ጊዜ ፡ በደል ፡ ይሆንበታል ፤ ወይም ፡ ርኩስነ
ቱን ፡ ሳያውቅ ፡ ርኩስን ፡ ሰው ፡ ቢነካ ÷ በማና
ቸውም ፡ ርኵሰት ፡ ቢረክስ ÷ ነገሩ ፡ በታወቀው ፡
፬ ፡ ጊዜ ፡ በደል ፡ ይሆንበታል ። ማናቸውም ፡
ሰው ፡ ሳያውቅ ፡ ክፉን ፡ ወይም ፡ መልካምን ፡
ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ሳያስብ ፡ በከንፈሩ ፡ ተናግሮ ፡
ቢምል ፤ ሳያስብ ፡ የማለው ፡ ስለ ፡ ማናቸውም ፡
ነገር ፡ ቢሆን ፤ በታወቀው ፡ ጊዜ ፡ ከዚህ ፡ ነገር ፡
፭ ፡ በአንዱ ፡ በደለኛ ፡ ይሆናል ። ከእነዚህ ፡ ነገ
ሮች ፡ በአንዲቱ ፡ በደለኛ ፡ ሲሆን ÷ የሠራውን ፡
፮ ፡ ኃጢአት ፡ ይናዘዛል ። ስለ ፡ ሠራው ፡ ኃጢ
አት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የበደል ፡ መሥዋዕት ፡
ያመጣል ፤ እርሱም ፡ ከመንጋው ፡ የበግ ፡
ወይም ፡ የፍየል ፡ እንስት ፡ ለኃጢአት ፡ መሥ
ዋዕት ፡ ይሆናል ፤ ካህኑም ፡ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡
ያስተሰርይለታል ።

፯ ፡ ስለ ፡ ሠራው ፡ ኃጢአት ፡ ለበደል ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ጠቦትን ፡ ለማምጣት ፡ ገንዘቡ ፡ ያልበቃ ፡
እንደ ፡ ሆነ ÷ ሁለት ፡ ዋኖሶች ፡ ወይም ፡ ሁለት ፡
የርግብ ፡ ግልገሎች ÷ አንዱን ፡ ለኃጢአት ፡
መሥዋዕት ፡ ሁለተኛውንም ፡ ለሚቃጠል ፡
መሥዋዕት ÷ ለእግዚአብሔር ፡ ያቀርባል ።
፰ ፡ ወደ ፡ ካህኑም ፡ ያመጣቸዋል ፤ እርሱም ፡ አስ
ቀድሞ ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ የሆነውን ፡
ያቀርባል ÷ ራሱንም ፡ ከአንገቱ ፡ ይቈለምመ
፱ ፡ ዋል ÷ ነገር ፡ ግን ፡ አይቈርጠውም ። ከኃጢ
አቱም ፡ መሥዋዕት ፡ ደም ፡ በመሠዊያው ፡ ግድ
ግዳ ፡ ላይ ፡ ይረጨዋል ፤ የተረፈውም ፡ ደም ፡
ከመሠዊያው ፡ በታች ፡ ይንጠፈጠፋል ፤ እርሱ ፡
፲ ፡ የኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ነው ። እንደ ፡ ሥር
ዓቱም ፡ ሁለተኛውን ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ያዘጋጀዋል ። ካህኑም ፡ ስለ ፡ ሠራው ፡
ኃጢአት ፡ ያስተሰርይለታል ÷ እርሱም ፡ ይቅር ፡
ይባላል ።

፲፩ ፡ ሁለት ፡ ዋኖሶች ፡ ወይም ፡ ሁለት ፡ የርግብ ፡
ግልገሎች ፡ ለማምጣት ፡ ገንዘቡ ፡ ያልበቃ ፡
እንደ ፡ ሆነ ÷ ስለ ፡ ሠራው ፡ ኃጢአት ፡ የኢፍ ፡

መስፈሪያ ፡ አሥረኛ ፡ ክፍል ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርበዋል ፤ የኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ነውና ፡ ዘይት ፡ አያፈስስበትም ፥ ዕጣንም ፡ አይጨምርበትም ። **፲፪** ወደ ፡ ካህኑም ፡ ያመጣዋል ፥ ካህኑም ፡ መታሰቢያው ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ከእርሱ ፡ እፍኝ ፡ ሙሉ ፡ ይውሰድ ፥ ለእግዚአብሔርም ፡ በእሳት ፡ በተቃጠለው ፡ ቍርባን ፡ ላይ ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ፤ እርሱም ፡ የኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ነው ። **፲፫** ካህኑም ፡ ከእነዚያ ፡ በአንዳቸው ፡ ስለ ፡ ሠራው ፡ ኃጢአት ፡ ያስተሰርይለታል ፥ እርሱም ፡ ይቅር ፡ ይባላል ። የተረፈውም ፡ እንደ ፡ እህል ፡ ቍርባን ፡ ለካህኑ ፡ ይሆናል ።

**፲፬** እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ **፲፭** ተናገረው ፡— ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ቢበድል ፥ ሳያውቅም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በተቀደሰው ፡ በማናቸውም ፡ ነገር ፡ ኃጢአትን ፡ ቢሠራ ፥ ለበደል ፡ መሥዋዕት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ከመንጋ ፡ ነውር ፡ የሌለበትን ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ያቀርባል ፤ እንደ ፡ ግምጋሚህ ፡ መጠን ፡ በብር ፡ ሰቅል ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ ለበደል ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርበዋል ። **፲፮** በተቀደሰ ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ሠራው ፡ ኃጢአት ፡ ዕዳ ፡ ይከፍላል ፥ አምስተኛውንም ፡ እጅ ፡ ይጨምርበታል ፥ ለካህኑም ፡ ይሰጠዋል ። ካህኑም ፡ በበደል ፡ መሥዋዕት ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ያስተሰርይለታል ፥ እርሱም ፡ ይቅር ፡ ይባላል ።

**፲፯** ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ኃጢአት ፡ ቢሠራ ፥ እግዚአብሔርም ፡— አትሥሩ ፡ ካላቸው ፡ ትእዛዛት ፡ አንዲቱን ፡ ቢተላለፍ ፥ ባያውቅም ፥ ያ ፡ ሰው ፡ በደለኛ ፡ ነው ፥ ኃጢአቱንም ፡ ይሸከማል ። **፲፰** ነውር ፡ የሌለበትን ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ከመንጋው ፡ ለበደል ፡ መሥዋዕት ፡ እንደ ፡ ግምጋሚህ ፡ መጠን ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ያመጣዋል ፤ ካህኑም ፡ ሳያውቅ ፡ ስለ ፡ ሳተው ፡ ስሕተት ፡ ያስተሰርይለታል ፥ እርሱም ፡ ይቅር ፡ ይባላል ። **፲፱** እርሱም ፡ የበደል ፡ መሥዋዕት ፡ ነው ፤ በእውነት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በደለኛ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

**፩** እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ **፪** ተናገረው ፡— ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ኃጢአትን ፡ ቢሠራ ፥ እግዚአብሔርንም ፡ ቢበድል ፥ ያኖረበትን ፡ አደራ ፡ ወይም ፡ ብድር ፡ ወስዶ ፡ ባልንጀራውን ፡ ቢክድ ፥ ወይም ፡ ቢቀማ ፥ ወይም ፡ **፫** በባልንጀራው ፡ ላይ ፡ ግፍ ፡ ቢያደርግ ፥ ወይም ፡ የጠፋውን ፡ ነገር ፡ ቢያገኝ ፥ ያንንም ፡ ሸሽጎ ፡ በሐሰት ፡ ቢምል ፥ ሰው ፡ ከሚያደርጋቸው ፡ ከእነዚህ ፡ ነገሮች ፡ ሁሉ ፡ በአንዲቱ ፡ ቢበድል ፥ **፬** እርሱ ፡ ኃጢአትን ፡ ሠርቶ ፡ በደለኛ ፡ ቢሆን ፥ በቅሚያ ፡ የወሰደውን ፡ ወይም ፡ በግፍ ፡ የተቀበለውን ፡ ወይም ፡ የተሰጠውን ፡ አደራ ፡ ወይም ፡ **፭** ጠፍቶ ፡ ያገኘውን ፥ ወይም ፡ በሐሰት ፡ የማለበትን ፡ ነገር ፡ ይመልስ ፤ በሙሉ ፡ ይመልስ ፥ ከዚያም ፡ በላይ ፡ አምስተኛውን ፡ ክፍል ፡ ጨምሮ ፡ የበደሉን ፡ መሥዋዕት ፡ በሚያቀርብበት ፡ ቀን ፡ ለባለ ፡ ገንዘቡ ፡ ይስጠው ። **፮** ስለ ፡ በደል ፡ መሥዋዕትም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ከመንጋው ፡ ነውር ፡ የሌለበትን ፡ አውራ ፡ በግ ፡ እንደ ፡ ግምጋሚህ ፡ መጠን ፡ ስለ ፡ በደል ፡ መሥዋዕት ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ያምጣ ። **፯** ካህኑም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያስተሰርይለታል ፥ ስለዚያም ፡ ስላደረገው ፡ በደል ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡ ይባላል ።

**፰** እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ **፱** ተናገረው ፡— አሮንንና ፡ ልጆቹን ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ እዘዛቸው ፡— የሚቃጠለው ፡ የመሥዋዕቱ ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የሚቃጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ባለው ፡ እንጨት ፡ ላይ ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ እስኪጸባ ፡ ድረስ ፡ ይሆናል ፤ እሳቱም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ዘወትር ፡ ይነድዳል ። **፲** ካህኑም ፡ የበፍታ ፡ ቀሚስና ፡ የበፍታ ፡ ሱሪ ፡ በሥጋው ፡ ላይ ፡ ይለብሳል ፤ በመሠዊያውም ፡ ላይ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ እሳቱ ፡ ከበላው ፡ በኋላ ፡ አመዱን ፡ አንሥቶ ፡ በመሠዊያው ፡ አጠገብ ፡ ያፈስሰዋል ። **፲፩** ልብሱንም ፡ ያወልቃል ፥ ሌላም ፡ ልብስ ፡ ይለብሳል ፤ አመዱንም ፡ ተሸክሞ ፡ ከሰፈሩ ፡ ንጹሕ ፡ ስፍራ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ያወጣዋል ። **፲፪** እሳቱም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ዘወትር ፡ ይነድዳል ፥ አይጠፋም ፤ ካህኑም ፡ ማለዳ ፡ ማለዳ ፡ እንጨት ፡ ያቃጥልበታል ፤ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ ይረበርባል ፤ በዚያም ፡ የደኅንነትን ፡ መሥዋዕት ፡ ስብ ፡ ያቃጥላል ። **፲፫** ዘወትር ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ እሳት ፡ ይነድዳል ፤ አይጠፋም ።

**፲፬** የእህሉም ፡ ቍርባን ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የአሮን ፡ ልጆች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በመሠዊያው ፡ ፊት ፡ ያቀርቡታል ። **፲፭** ካህኑም ፡ ከእህሉ ፡ ቍርባን ፡ መልካሙን ፡ ዱቄት ፡ ከዘይት ፡ ጋር ፡ እፍኝ ፡ ሙሉ ፥ ደግሞም ፡ በእህሉ ፡ ቍርባን ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ዕጣን ፡ ሁሉ ፡ ያነሣል ፥ ለእግዚአብሔርም ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ ለመታሰቢያ ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ። **፲፮** ከእርሱም ፡ የተረፈውን ፡ አሮንና ፡ ልጆቹ ፡ ይበሉታል ፤ ቂጣ ፡ ሆኖ ፡ በተቀደሰ ፡ ስፍራ ፡ ይበላል ፤ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ዙሪያ ፡ ባለው ፡ አደባባይ ፡ ይበሉታል ። **፲፯** በእርሾ ፡ በክቶ ፡ አይጋገርም ። እርሱን ፡ ከእሳቱ ፡ ቍርባኔ ፡ ለእነርሱ ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ እንዲሆን ፡ ሰጠሁ ፤ እርሱም ፡ እንደ ፡ ኃጢአትና ፡ እንደ ፡ በደል ፡ መሥዋዕት ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱሳን ፡ ነው ። **፲፰** ለእግዚአብሔር ፡ ከቀረበ ፡ ከእሳት ፡ ቍርባን ፡ ለዘለዓለም ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ እድል ፡ ፈንታቸው ፡ እንዲሆን ፡ ከአሮን ፡ ልጆች ፡ ወንዶቹ ፡ ሁሉ ፡ ይበሉታል ። የሚነካቸው ፡ ሁሉ ፡ ቅዱስ ፡ ይሆናል ።

**፲፱** እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ **፳** ተናገረው ፡— በተቀቡበት ፡ ቀን ፡ የኢፍ ፡ መስ

ፈሪያ ፡ አሥረኛ ፡ ክፍል ፡ መልካሙን ፡ዱቄት ፡ እኵሌታውን ፡ በጥዋት ፥ እኵሌታውንም ፡ በማታ ፡ ለዘወትር ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ አድርገው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚያቀርቡት ፡ የአሮ ፳፩፤ ንና ፡ የልጆቹ ፡ ቍርባን ፡ ይህ ፡ ነው ። ከዘይት ፡ ጋር ፡ በምጣድ ፡ ላይ ፡ ይደረጋል ፤ ሲለወስ ፡ ታገ ባዋለህ ፤ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እን ዲሆን ፡ የእህሉን ፡ ቍርባን ፡ ቈራርሰህ ፡ ታቀር ፳፪፤ ባዋለህ ። ከልጆቹም ፡ በአባቱ ፡ ፋንታ ፡ የተቀ ባው ፡ ካህን ፡ ያቀርበዋል ። ለዘላለም ፡ ሥር ዓት ፡ እንዲሆን ፡ ፈጽሞ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይቃ ፳፫፤ ጠላል ። ካህኑም ፡ የሚያቀርበው ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሞ ፡ ይቃጠላል ፤ ከእርሱም ፡ አንዳች ፡ አይበላም ።

፳፬፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ፳፭፤ ተናገረው ፡— አሮንንና ፡ ልጆቹን ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ተናገራቸው ፡— የኃጢአት ፡ መሥዋ ዕት ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የሚቃጠል ፡ መሥዋ ዕት ፡ በሚታረድበት ፡ ስፍራ ፡ የኃጢአቱ ፡ መሥ ዋዕት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይታረዳል ፤ ፳፮፤ እርሱ ፡ ቅዱሰ ፡ ቅዱሳን ፡ ነው ። ለኃጢአት ፡ የሚሠዋው ፡ ካህን ፡ ይበላዋል ፤ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ዙሪያ ፡ ባለው ፡ አደባባይ ፡ በተቀደሰ ፡ ፳፯፤ ስፍራ ፡ ይበላል ። ሥጋውን ፡ የሚነካ ፡ ሁሉ ፡ ቅዱስ ፡ ይሆናል ፤ ማናቸው ፡ ልብስ ፡ ደም ፡ ቢረ ጭበት ፡ የተረጨበትን ፡ በተቀደሰ ፡ ስፍራ ፡ ፳፰፤ ታጥበዋለህ ። የሚቀቀልበትም ፡ ሸክላ ፡ ይሰበ ራል ፤ በናስም ፡ ዕቃ ፡ ቢቀቀል ፡ ይፈገፈጋል ፥ ፳፱፤ በውኃም ፡ ይለቀለቃል ። ከካህናት ፡ ወገን ፡ የሆነ ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ ይበላል ፤ እርሱ ፡ ፴፤ ቅዱሰ ፡ ቅዱሳን ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ በመቅደሱ ፡ ውስጥ ፡ ለማስተስረያ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ከደሙ ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ የሚገባው ፡ የኃጢ አት ፡ መሥዋዕት ፡ ሁሉ ፡ አይበላም ፤ በእሳት ፡ ይቃጠላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩፤ የበደል ፡ መሥዋዕት ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ፪፤ ቅዱሰ ፡ ቅዱሳን ፡ ነው ። የሚቃጠለውን ፡ መሥ ዋዕት ፡ በሚያርዱበት ፡ ስፍራ ፡ የበደሉን ፡ መሥ ዋዕት ፡ ያርዱታል ፤ ደሙንም ፡ በመሠዊያው ፡ ፫፤ ላይ ፡ በዙሪያው ፡ ይረጨዋል ። ስቡንም ፡ ሁሉ ፥ ላቱንም ፥ የሆድ ፡ ዕቃውንም ፡ የሚሸፍነውን ፡ ፬፤ ስብ ፡ ያቀርበዋል ። ሁለቱንም ፡ ኵላሊቶች ፥ በእነርሱም ፡ ላይና ፡ በጐድኑ ፡ አጠገብ ፡ ያለውን ፡ ስብ ፥ በጕበቱም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ መረብ ፡ ከኵ ፭፤ ላሊቶቹ ፡ ጋር ፡ ይወስዳል ። ካህኑም ፡ ለእግዚ አብሔር ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ እንዲሆን ፡ በመሠ ዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ፤ እርሱ ፡ የበደል ፡ ፮፤ መሥዋዕት ፡ ነው ። ከካህናት ፡ ወገን ፡ የሆነ ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ ይበላዋል ፤ በተቀደሰ ፡ ስፍራ ፡ ፯፤ ይበሉታል ፤ ቅዱሰ ፡ ቅዱሳን ፡ ነው ። የኃጢ አት ፡ መሥዋዕት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንዲሁ ፡ የበደል ፡ መሥዋዕት ፡ ነው ፤ ለሁለቱ ፡ አንድ ፡ ሕግ ፡ ነው ፤

በእርሱ ፡ የሚያስተሰርይ ፡ ካህን ፡ ይወስደዋል ። ፰፤ የማናቸውንም ፡ ሰው ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋ ዕት ፡ የሚያቀርብ ፡ ካህን ፡ ያቀረበው ፡ የሚቃ ጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ ቁርበት ፡ ለዚያው ፡ ካህን ፡ ይሆናል ። ፱፤ በእቶን ፡ የተጋገረው ፡ የእህል ፡ ቍር ባን ፡ ሁሉ ፥ በመቀቀያም ፡ ወይም ፡ በምጣድ ፡ የበሰለው ፡ ሁሉ ፡ ለሚያቀርበው ፡ ካህን ፡ ይሆ ናል ። ፲፤ በዘይትም ፡ የተለወሰው ፡ ወይም ፡ የደ ረቀው ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ሁሉ ፡ ለአሮን ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ይሆናል ፤ ለሁሉም ፡ ይሆናል ።

፲፩፤ ሰው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚያቀርበው ፡ የደ ኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ። ፲፪፤ ለምስ ጋና ፡ ቢያቀርበው ፥ ከምስጋናው ፡ መሥዋዕት ፡ ጋር ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ የቂጣ ፡ እንጎቻ ፥ በዘ ይትም ፡ የተቀባ ፡ ስስ ፡ ቂጣ ፥ በዘይትም ፡ የተ ለወሰ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ ያቀርባል ። ፲፫፤ ለምስ ጋና ፡ የሚሆነውን ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ ባቀረበ ፡ ጊዜ ፡ እርሾ ፡ ያለበትን ፡ ኅብስት ፡ ያቀ ርባል ። ፲፬፤ ከቍርባኑም ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የማንሣት ፡ ቍርባን ፡ እንዲሆን ፡ ከእነርሱ ፡ አን ዱን ፡ ያነሣል ። እርሱም ፡ የደኅንነትን ፡ መሥ ዋዕት ፡ ደም ፡ ለሚረጨው ፡ ካህን ፡ ይሆናል ።

፲፭፤ ለምስጋና ፡ የሚሆነው ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋ ዕት ፡ ሥጋ ፡ በሚቀርብበት ፡ ቀን ፡ ይበሉታል ፤ ከእርሱ ፡ እስከ ፡ ነገ ፡ ምንም ፡ አያድርም ። ፲፮፤ የቍ ርባኑም ፡ መሥዋዕት ፡ የስእለት ፡ ወይም ፡ የፈ ቃድ ፡ ቢሆን ፥ መሥዋዕቱ ፡ በሚቀርብበት ፡ ቀን ፡ ይብሉት ፤ ከእርሱም ፡ የቀረውን ፡ በነጋው ፡ ይብ ሉት ፤ ፲፯፤ ከመሥዋዕቱም ፡ ሥጋ ፡ እስከ ፡ ሦስተ ኛው ፡ ቀን ፡ የሚቆየው ፡ በእሳት ፡ ይቃጠላል ። ፲፰፤ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ከደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ ሥጋ ፡ ቢበላ ፥ አይሠምርም ፤ ላቀረበው ፡ ሰው ፡ የተጠላ ፡ ይሆንበታል ፡ እንጂ ፡ ቍርባን ፡ ሆኖ ፡ አይቈጠርለትም ፤ ከእርሱም ፡ ቢበላ ፡ ኃጢአ ቱን ፡ ይሸከማል ።

፲፱፤ ርኩስ ፡ ነገር ፡ የሚነካውን ፡ ሥጋ ፡ አይብሉት ፤ በእሳት ፡ ይቃጠል ። ንጹሕ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ከሥጋው ፡ ይብላ ። ፳፤ ሰውም ፡ የረከሰ ፡ ቢሆን ፥ ለእግዚአብሔርም ፡ ከሆነው ፡ ከደኅን ነት ፡ መሥዋዕት ፡ ሥጋ ፡ ቢበላ ፥ ያ ፡ ሰው ፡ ከሕ ዝቡ ፡ ተለይቶ ፡ ይጥፋ ። ፳፩፤ ማናቸውንም ፡ ርኩስ ፡ ነገር ፡ ቢነካ ፥ የሰውን ፡ ወይም ፡ የረከሰን ፡ እን ስሳ ፡ ወይም ፡ ሌላውን ፡ የተጠላ ፡ ርኩስን ፡ ቢነካ ፥ ለእግዚአብሔርም ፡ ከሆነው ፡ ከደኅንነት ፡ መሥ ዋዕት ፡ ሥጋ ፡ ቢበላ ፥ ያ ፡ ሰው ፡ ከሕዝቡ ፡ ተለ ይቶ ፡ ይጥፋ ።

፳፪፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፳፫፤ ተናገረው ፡— የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ተናገራቸው ፡— የበሬ ፡ ወይም ፡ የበግ ፡ ወይም ፡ የፍየል ፡ ስብ ፡ ከቶ ፡ አትብሉ ። ፳፬፤ የሞ ተውን ፡ ስብ ፥ አውሬ ፡ የሰበረውንም ፡ ስብ ፡ ለሌላ ፡ ተግባር ፡ አድርጉት ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ ምንም ፡ አትብሉ ፤ ፳፭፤ ለእግዚአብሔር ፡ በእሳት ፡ ከሚቀርበው ፡ ከእንስሳ ፡ ስብ ፡ የሚበላ ፡ ሁሉ ፥

ያ ፡ የበላ ፡ ሰው ፡ ከሕዝቡ ፡ መካከል ፡ ተለ
፳፮ ይቶ ፡ ይጠፋልና ። በማደሪያዎቻችሁም ፡ ሁሉ ፡
የወፍ ፡ ወይም ፡ የእንስሳ ፡ ደም ፡ ቢሆን ፡ አት
፳፯ ብሉ ። ደም ፡ የሚበላ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ያ ፡ ሰው ፡
ከሕዝቡ ፡ መካከል ፡ ተለይቶ ፡ ይጥፋ ።
፳፰ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፳፱ ተናገረው ፡— የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡
ብለህ ፡ ተናገራቸው ፡— ለእግዚአብሔር ፡ የደኅ
ንነት ፡ መሥዋዕት ፡ የሚያቀርብ ፡ ሰው ፡ ቍር
ባኑን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ከደኅንነቱ ፡ መሥዋ
፴ ዕት ፡ ያመጣል ። የእርሱ ፡ እጆች ፡ ለእግዚአ
ብሔር ፡ የእሳቱን ፡ ቍርባን ፡ ያመጣሉ ፤ ፍርም
ባው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለመወዝወዝ ፡
ቍርባን ፡ ይወዘውዝ ፡ ዘንድ ፡ ስቡንና ፡ ፍርም
፴፩ ባውን ፡ ያመጣል ። ካህኑም ፡ ስቡን ፡ በመሠዊ
ያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥላል ፤ ፍርምባውም ፡ ለአሮ
፴፪ ንና ፡ ለልጆቹ ፡ ይሁን ። ከደኅንነት ፡ መሥዋዕ
ታችሁ ፡ ቀኙ ፡ ወርቹን ፡ ለማንሣት ፡ ቍርባን ፡
፴፫ እንዲሆን ፡ ለካህኑ ፡ ትሰጡታላችሁ ። ከአሮ
ንም ፡ ልጆች ፡ የደኅንነትን ፡ መሥዋዕት ፡ ደሙ
ንና ፡ ስቡን ፡ ለሚያቀርብ ፡ ለእርሱ ፡ ቀኙ ፡ ወርቹ ፡
፴፬ እድል ፡ ፈንታው ፡ ይሆናል ። የሚወዘወዘውን ፡
ፍርምባና ፡ የሚነሣውን ፡ ወርች ፡ ከእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ከደኅንነት ፡ መሥዋዕታቸው ፡ ወስጄ
አለሁ ፥ ለካህኑ ፡ ለአሮንና ፡ ለልጆቹም ፡ ለዘላ
ለም ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ እንዲሆን ፡ ከእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ዘንድ ፡ ሰጥቼአቸዋለሁ ።
፴፭ እግዚአብሔርን ፡ በክህነት ፡ ያገለግሉት ፡
ዘንድ ፡ በቀረበቻው ፡ ቀን ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ከሆነ ፡ ከእሳት ፡ ቍርባን ፡ የአሮንና ፡ የልጆቹ ፡
፴፮ እድል ፡ ፈንታ ፡ ይህ ፡ ነው ። ለልጅ ፡ ልጃቸው ፡
ለዘላለም ፡ እድል ፡ ፈንታቸው ፡ እንዲሆን ፡ በቀባ
ቸው ፡ ቀን ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ይሰጡአቸው ፡
ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያዘዘው ፡ ይህ ፡ ነው ።
፴፯ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕትና ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፥
የኃጢአትና ፡ የበደል ፡ መሥዋዕት ፥ የቅድስ
ናና ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡
፴፰ ነው ። እግዚአብሔር ፡ በሲና ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ቍር
ባናቸውን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡
ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ባዘዘ ፡ ጊዜ ፡ በሲና ፡
ተራራ ፡ ለሙሴ ፡ ያዘዘው ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪ ተናገረው ፡— አሮንን ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ልጆ
ቹን ፥ ልብሱንም ፥ የቅብዓቱንም ፡ ዘይት ፥ ለኃ
ጢአት ፡ መሥዋዕትም ፡ የሆነውን ፡ ወይፈን ፥
ሁለቱንም ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ የቂጣውንም ፡ እን
፫ ጀራ ፡ ሌማት ፡ ውሰድ ፤ ማኅበሩንም ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ሰብስባ
፬ ቸው ። ሙሴም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡
አደረገ ፤ ማኅበሩ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡
፭ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ተሰበሰቡ ። ሙሴም ፡ ማኅበ
ሩን ፡— እግዚአብሔር ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ ያዘ
ዘው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አላቸው ።
፮ ሙሴም ፡ አሮንንና ፡ ልጆቹን ፡ አቀረበ ፥ በው
፯ ኃም ፡ አጠባቸው ። ሸሚዝም ፡ አለበሰው ፥
በመታጠቂያም ፡ አስታጠቀው ፥ ቀሚስም ፡ አለ
በሰው ፥ ኤፉድም ፡ ደረበለት ፥ በብልሃትም ፡
በተጠለፈ ፡ ቋድ ፡ አስታጠቀውና ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡
፰ አሰረው ። የደረት ፡ ኪስ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ አደረገ ፤
በደረቱ ፡ ኪስም ፡ ውስጥ ፡ ኡሪምንና ፡ ቱሚ
፱ ምን ፡ አኖረበት ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡
እንዳዘዘው ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ መጠምጠሚያውን ፡
አደረገ ፤ በመጠምጠሚያውም ፡ ላይ ፡ በፊቱ ፡
በኩል ፡ የተቀደሰውን ፡ አክሊል ፥ ቅጠል ፡ የሚ
መስለውን ፡ የወርቅ ፡ ምልክት ፥ አደረገ ።
፲ ሙሴም ፡ የቅብዓቱን ፡ ዘይት ፡ ወሰደ ፥ ማደ
ሪያውንና ፡ በውስጡ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ቀብቶ ፡
፲፩ ቀደሳቸው ። ከእርሱም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡
ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ረጨ ፤ ይቀድሳቸውም ፡ ዘንድ ፡
መሠዊያውንና ፡ ዕቃውን ፡ ሁሉ ፥ የመታጠቢ
፲፪ ያውን ፡ ሰንና ፡ መቀመጫውን ፡ ቀባ ። ከቅብዓ
ቱም ፡ ዘይት ፡ በአሮን ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ አፈሰሰ ፥
፲፫ ይቀድሰውም ፡ ዘንድ ፡ ቀባው ። እግዚአብሔ
ርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ ሙሴ ፡ የአሮንን ፡
ልጆች ፡ አቀረበ ፥ ቀሚሶችንም ፡ አለበሳቸው ፥
በመታጠቂያም ፡ አስታጠቃቸው ፥ ቆብም ፡
ደፋባቸው ።
፲፬ የኃጢአትንም ፡ መሥዋዕት ፡ ወይፈን ፡ አቀ
ረበ ፤ አሮንና ፡ ልጆቹም ፡ በኃጢአቱ ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ወይፈን ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ እጆቻቸውን ፡ ጫኑ ።
፲፭ አረደውም ፤ ሙሴም ፡ ደሙን ፡ ወስዶ ፡ በጣቱ ፡
የመሠዊያውን ፡ ቀንዶች ፡ ዙሪያ ፡ ቀባ ፥ መሠ
ዊያውንም ፡ አነጻው ፤ ደሙንም ፡ ከመሠዊ
ያው ፡ በታች ፡ አፈሰሰው ፥ ያስተሰርይለትም ፡
፲፮ ዘንድ ፡ ቀደሰው ። በሆድ ፡ ዕቃውም ፡ ላይ ፡
ያለውን ፡ ስብ ፡ ሁሉ ፥ የጕበቱንም ፡ መረብ ፥
ሁለቱንም ፡ ኵላሊቶች ፡ ስባቸውንም ፡ ወሰደ ፤
ሙሴም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ አቃጠለው ።
፲፯ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ ወይ
ፈኑን ፥ ቁርበቱንም ፥ ሥጋውንም ፥ ፈርሱ
ንም ፡ ከሰፈሩ ፡ ውጭ ፡ በእሳት ፡ አቃጠለ ።
፲፰ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕትም ፡ የሚሆን ፡
አውራ ፡ በግ ፡ አቀረበ ፤ አሮንና ፡ ልጆቹም ፡
በአውራው ፡ በግ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ እጆቻቸውን ፡
፲፱ ጫኑ ። አረደውም ፤ ሙሴም ፡ ደሙን ፡ በመ
፳ ሠዊያው ፡ ዙሪያ ፡ ረጨው ። አውራውንም ፡
በግ ፡ በየብልቱ ፡ ቈረጠ ፤ ሙሴም ፡ ጭንቅላ
፳፩ ቱን ፡ ብልቶቹንም ፡ ስቡንም ፡ አቃጠለ ። የሆድ ፡
ዕቃውንና ፡ እግሮቹንም ፡ በውኃ ፡ አጠበ ፤
ሙሴም ፡ አውራውን ፡ በግ ፡ ሁሉ ፡ በመሠዊ
ያው ፡ ላይ ፡ አቃጠለው ፤ ይህ ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡
እንዲሆን ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ነበረ ፤
እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ ለእግዚ
አብሔር ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ነበረ ።
፳፪ ለቅድስናም ፡ የሚሆነውን ፡ ሁለተኛውን ፡
አውራ ፡ በግ ፡ አቀረበ ፤ አሮንና ፡ ልጆቹም ፡

በአውራው ፡ በግ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ እጆቻቸውን ፡
፳፫፡ ጫኑ ። አረደውም ፤ ሙሴም ፡ ከደሙ ፡ ወስዶ ፡
የአሮንን ፡ የቀኝ ፡ ጆሮውን ፡ ጫፍ ፥ የቀኝ ፡
እጁንም ፡ አውራ ፡ ጣት ፡ የቀኝ ፡ እግሩንም ፡
፳፬፡ አውራ ፡ ጣት ፡ አስነካው ። የአሮንንም ፡ ልጆች ፡
አቀረበ ፤ ሙሴም ፡ የቀኝ ፡ ጆሮአቸውን ፡ ጫፍ ፥
የቀኝ ፡ እጃቸውንም ፡ አውራ ፡ ጣት ፥ የቀኝ ፡
እግራቸውንም ፡ አውራ ፡ ጣት ፡ ከደሙ ፡ አስነካ ፤
ሙሴም ፡ ደሙን ፡ በመሠዊያው ፡ ዙሪያ ፡ ረጨ ።
፳፭፡ ስቡንና ፡ ላቱን ፥ በሆድ ፡ ዕቃውም ፡ ላይ ፡ ያለ
ውን ፡ ስብ ፡ ሁሉ ፥ የጕበቱንም ፡ መረብ ፥ ሁለ
ቱንም ፡ ኵላሊቶች ፡ ስባቸውንም ፥ ቀኝ ፡ ወር
፳፮፡ ቹንም ፡ ወሰደ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ካለው ፡
ከቂጣው ፡ እንጀራ ፡ ሌማት ፡ አንድ ፡ የቂጣ ፡
እንጐቻ ፥ አንድም ፡ የዘይት ፡ እንጀራ ፥ አን
ድም ፡ ስስ ፡ ቂጣ ፡ ወስዶ ፡ በስቡና ፡ በቀኝ ፡
፳፯፡ ወርቹ ፡ ላይ ፡ አኖራቸው ። ሁሉንም ፡ በአሮ
ንና ፡ በልጆቹ ፡ እጆች ፡ ላይ ፡ አደረገ ፥ በእግ
ዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ለመወዝወዝ ፡ ቍርባን ፡
፳፰፡ ወዘወዛቸው ። ሙሴም ፡ ከእጃቸው ፡ ተቀ
ብሎ ፡ በመሠዊያው ፡ በሚቃጠለው ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ላይ ፡ አቃጠለው ፤ የጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ መቀ
ደሻ ፡ ነበረ ። እርሱም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የእ
፳፱፡ ሳት ፡ ቍርባን ፡ ነበረ ። ሙሴም ፡ ፍርምባውን ፡
ወስዶ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለመወዝወዝ ፡
ቍርባን ፡ ወዘወዘው ፤ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡
እንዳዘዘው ፡ ይህ ፡ ለቅድስና ፡ ከታረደው ፡
አውራ ፡ በግ ፡ የሙሴ ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ ሆነ ።
፴፡ ሙሴም ፡ ከቅብዓቱ ፡ ዘይትና ፡ በመሠዊያው ፡
ላይ ፡ ካለው ፡ ከደሙ ፡ ወስዶ ፡ በአሮንና ፡ በል
ብሱ ፡ ላይ ፥ በልጆቹና ፡ በልጆቹ ፡ ልብስ ፡ ላይ ፡
ረጨው ፤ አሮንንና ፡ ልብሱንም ፥ ልጆቹንም ፥
የልጆቹንም ፡ ልብስ ፡ ቀደሰ ።
፴፩፡ ሙሴም ፡ አሮንንና ፡ ልጆቹን ፡ አላቸው ፡—
ሥጋውን ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡
ቀቅሉ ፤ አሮንና ፡ ልጆቹ ፡ ይበሉታል ፡ ብዬ ፡
እንዳዘዝሁ ፡ በዚያ ፡ እርሱንና ፡ በሌማቱ ፡ ያለ
፴፪፡ ውን ፡ የቅድስናውን ፡ እንጀራ ፡ ብሉ ። ከሥጋ
ውና ፡ ከእንጀራውም ፡ የተረፈውን ፡ በእሳት ፡
፴፫፡ ታቃጥሉታላችሁ ። ሰባት ፡ ቀን ፡ ይክናችኋ
ልና ፡ የክህነታችሁ ፡ ቀን ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡
ሰባት ፡ ቀን ፡ ከማኅበሩ ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ አት
፴፬፡ ውጡ ። በዚህ ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ተደረገ ፡ ለእና
ንተ ፡ ለማስተስረያ ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ እንዲሁ ፡
፴፭፡ እግዚአብሔር ፡ አዘዘ ። እግዚአብሔር ፡ እን
ዲሁ ፡ አዝዞኛልና ፡ እንዳትሞቱ ፡ በመገናኛው ፡
ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ሌሊቱንና ፡ ቀኑን ፡ ሰባት ፡
ቀን ፡ ተቀመጡ ፥ የእግዚአብሔርንም ፡ ሥር
፴፮፡ ዓት ፡ ጠብቁ ። አሮንና ፡ ልጆቹም ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ ያዘዘውን ፡ ሁሉ ፡ አደረጉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩፡ በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ ሙሴ ፡
አሮንንና ፡ ልጆቹን ፡ የእስራኤልንም ፡ ሽማግሌ
ዎች ፡ ጠራ ። አሮንንም ፡ አለው ፡— ስለ ፡ ኃጢ ፪፡
አት ፡ መሥዋዕት ፡ ከመንጋው ፡ እምቦሳውን ፥
ስለሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ አውራውን ፡ በግ ፡
ነውር ፡ የሌለባቸውን ፡ ወስደህ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ፊት ፡ አቅርባቸው ። የእስራኤልንም ፡ ፫፡፬፡
ልጆች ፡— ዛሬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይገለጥላችኋ
ልና ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ አውራ ፡ ፍየ
ልን ፥ ለሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ ነውር ፡ የሌ
ለባቸውን ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ የሆናቸውን ፡ እም
ቦሳና ፡ ጠቦትን ፥ ለደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ በሬ
ንና ፡ አውራን ፡ በግ ፥ በዘይትም ፡ የተለወሰ ፡ የእ
ህልን ፡ ቍርባን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይሠዉ ፡
፭፡ ዘንድ ፡ ውሰዱ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ። ሙሴም ፡
ያዘዛቸውን ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡
አመጡ ፤ ማኅበሩም ፡ ሁሉ ፡ ቀርበው ፡ በእግ
፮፡ ዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቆሙ ። ሙሴም ፡— ታደር
ጉት ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያዘዘው ፡ ይህ ፡
ነው ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ ይገለጥላች
፯፡ ኋል ፡ አለ ። ሙሴም ፡ አሮንን ፡— ወደ ፡ መሠ
ዊያው ፡ ቀርበህ ፡ የኃጢአትህን ፡ መሥዋዕትና ፡
የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትህን ፡ ሠዋ ፥ ለራስ
ህና ፡ ለሕዝቡም ፡ አስተስርይ ፤ እግዚአብሔርም ፡
እንዳዘዘ ፡ የሕዝቡን ፡ ቍርባን ፡ አቅርብ ፡ አስተ
ስርይላቸውም ፡ አለው ።
፰፡ አሮንም ፡ ወደ ፡ መሠዊያው ፡ ቀርቦ ፡ ስለ ፡
ራሱ ፡ ኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ የሆነውን ፡ እም
፱፡ ቦሳ ፡ አረደ ። የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ደሙን ፡ አቀ
ረቡለት ፤ ጣቱንም ፡ በደሙ ፡ ውስጥ ፡ ነክሮ ፡
የመሠዊያውን ፡ ቀንዶች ፡ አስነካ ፥ ደሙንም ፡
፲፡ ከመሠዊያው ፡ በታች ፡ አፈሰሰው ። እግዚአብ
ሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ ከኃጢአቱ ፡ መሥ
ዋዕት ፡ ስቡንና ፡ ኵላሊቶቹን ፥ የጕበቱንም ፡
፲፩፡ መረብ ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ አቃጠለ ። ሥጋ
ውንና ፡ ቍርበቱንም ፡ ከሰፈሩ ፡ ውጭ ፡ በእሳት ፡
አቃጠለ ።
፲፪፡ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ አረደ ፤ የአ
ሮንም ፡ ልጆች ፡ ደሙን ፡ አመጡለት ፥ እርሱም ፡
፲፫፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ በዙሪያው ፡ ረጨው ። የሚ
ቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ በየብልቱ ፥ ራሱ
ንም ፡ አመጡለት ፤ እርሱም ፡ በመሠዊያው ፡
፲፬፡ ላይ ፡ አቃጠለው ። የሆድ ፡ ዕቃውንና ፡ እግሮቹ
ንም ፡ አጠበ ፤ በመሠዊያውም ፡ በሚቃጠለው ፡
መሥዋዕት ፡ ላይ ፡ አቃጠለው ።
፲፭፡ የሕዝቡንም ፡ ቍርባን ፡ አቀረበ ፤ ስለ ፡ ሕዝቡ ፡
ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ የሆነውን ፡ ፍየል ፡
ወስዶ ፡ አረደው ፥ ስለ ፡ ኃጢአትም ፡ እንደ ፡ ፊተ
፲፮፡ ኛው ፡ ሠዋው ። የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡
፲፯፡ አቀረበ ፥ እንደ ፡ ሥርዓቱም ፡ አደረገው ። የእህ
ሉንም ፡ ቍርባን ፡ አቀረበ ፥ ከእርሱም ፡ እፍኝ ፡
ሙሉ ፡ ወስዶ ፡ በጥዋት ፡ ከሚቃጠለው ፡ መሥ
ዋዕት ፡ ሌላ ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ አቃጠለው ።
፲፰፡ ስለ ፡ ሕዝቡ ፡ የሆነውን ፡ የደኅንነት ፡ መሥ
ዋዕት ፡ በሬውንና ፡ አውራውን ፡ በግ ፡ አረደ ፤
የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ደሙን ፡ አመጡለት ፥ በመ

፲፱ ሥዊያውም ፡ ላይ ፡ በዙሪያው ፡ ረጨው ፤ የበሬውንና ፡ የአውራውንም ፡ በግ ፡ ስብ ÷ ላቱንም ÷ የሆድ ፡ ዕቃውንም ፡ የሚሸፍነውን ፡ ስብ ÷ ኵላሊቶቹንም ÷ የጕበቱንም ፡ መረብ ፡ አመጡለት ።
፳ ስቡንም ፡ በፍርምባዎቹ ፡ ላይ ፡ አደረጉ ÷ ስቡ
፳፩ ንም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ አቃጠለ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ አሮን ፡ ፍርምባዎቹንና ፡ ቀኝ ፡ ወርቹን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለመወዝወዝ ፡ ቍርባን ፡ ወዘወዘው ።
፳፪ አሮንም ፡ እጆቹን ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ ዘረጋ ፡ በረከቸውም ፤ የኃጢአቱን ፡ የሚቃጠለውንም ፡ የደኅንነቱንም ፡ መሥዋዕት ፡ ከሠዋ ፡ በኋላ ፡
፳፫ ወረደ ። ሙሴና ፡ አሮንም ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ገቡ ፤ ወጡም ÷ ሕዝቡንም ፡ በረኩ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ ለሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ተገ
፳፬ ለጠ ። እሳትም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ÷ በመሠዊያውም ፡ ላይ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ስቡንም ፡ በላ ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ አይተው ፡ እልል ፡ አሉ ÷ በግምባራቸውም ፡ ወደቁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ናዳብና ፡ አብዩድ ፡ በየራሳቸው ፡ ጥናውን ፡ ወስደው ፡ እሳት ፡ አደረጉበት ÷ በላዩም ፡ ዕጣን ፡ አኖሩበት ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ እርሱ ፡ ያላዘዛቸውን ፡ ሌላ ፡
፪ እሳት ፡ አቀረቡ ። እሳትም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ወጥቶ ፡ በላቸው ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡
፫ ሞቱ ። ሙሴም ፡ አሮንን ፡— እግዚአብሔር ፡— ወደ ፡ እኔ ፡ በሚቀርቡ ፡ እቀደሳለሁ ÷ በሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ እከብራለሁ ፡ ብሎ ፡ የተናገረው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አለው ፤ አሮንም ፡ ዝም ፡ አለ ።
፬ ሙሴም ፡ የአሮንን ፡ አጎት ፡ የዑዝኤልን ፡ ልጆች ፡ ሚሳኤልንና ፡ ኤልጻፋንን ፡ ጠርቶ ፡— ቀረቡ ÷ ወንድሞቻችሁንም ፡ ከመቅደሱ ፡ ፊት ፡ አንሥታችሁ ፡ ከሰፈር ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ውሰዱአቸው ፡
፭ አላቸው ። እነርሱም ፡ ቀርበው ፡ አነሡአቸው ÷ ሙሴም ፡ እንዳለ ፡ በቀሚሳቸው ፡ ከሰፈር ፡ ወደ ፡
፮ ውጭ ፡ ወሰዱአቸው ። ሙሴም ፡ አሮንን ÷ ልጆቹንም ፡ አልዓዛርንና ፡ ኢታምርን ፡— እንዳትሞቱ ፡ በማኅበሩም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ቍጣ ፡ እንዳይወርድ ፡ ራሳችሁን ፡ አትንጩ ÷ ልብሳችሁንም ፡ አትቅደዱ ፤ እግዚአብሔር ፡ ስላቃጠለው ፡ ማቃጠል ፡ ግን ፡ ወንድሞቻችሁ ፡ የእስራኤል ፡
፯ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ያልቅሱ ። የእግዚአብሔር ፡ የቅብዓት ፡ ዘይት ፡ በላያችሁ ፡ ነውና ፡ እንዳትሞቱ ፡ ከመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ አትወጡም ፡ አላቸው ። እንደ ፡ ሙሴ ፡ ቃልም ፡ አደረጉ ።
፰ እግዚአብሔርም ፡ አሮንን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፱ ተናገረው ፡— እንዳትሞቱ ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ስትገቡ ፡ አንተና ፡ ልጆችህ ፡ የወይን ፡ ጠጅና ፡ የሚያሰክርን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አትጠጡ ፤ ይህም ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡
፲ ይሆናል ፤ በተቀደሰውና ፡ ባልተቀደሰው ÷ በርኩሱና ፡ በንጹሑም ፡ መካከል ፡ ትለያላችሁ ፤
፲፩ እግዚአብሔርም ፡ በሙሴ ፡ ቃል ፡ የነገራቸውን ፡ ሥርዓት ፡ ሁሉ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ታስተምራላችሁ ።
፲፪ ሙሴም ፡ አሮንን ÷ የተረፉለትንም ፡ ልጆቹን ፡ አልዓዛርንና ፡ ኢታምርን ፡ አላቸው ፡— ቅዱስ ፡ ቅዱሳን ፡ ነውና ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ከሆነው ፡ ከእሳት ፡ ቍርባን ፡ የቀረውን ፡ የእህሉን ፡ ቍርባን ፡ ውሰዱ ÷ ቂጣም ፡ አድርጋችሁ ፡ በመሠዊ
፲፫ ያው ፡ አጠገብ ፡ ብሉት ፡ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ አዝዞኛልና ÷ ለእግዚአብሔር ፡ ከሆነው ፡ ከእሳት ፡ ቍርባን ፡ ለአንተም ፡ ለልጆችህም ፡ የተሰጠ ፡ ሥርዓት ፡ ነውና ፡ በቅዱስ ፡ ስፍራ ፡ ትበ
፲፬ ሉታላችሁ ። እነዚህም ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከደኅንነት ፡ መሥዋዕቶች ፡ ለአንተና ፡ ለልጆችህ ፡ ሥርዓት ፡ እንዲሆኑ ፡ ስለ ፡ ተሰጡ ÷ የሚወዘወዘውን ፡ ፍርምባ ÷ የሚነሣውንም ፡ ወርች ፡ አንተ ÷ ከአንተ ፡ ጋርም ፡ ልጆችህ ÷ ሴቶች ፡ ልጆችህም ፡ በንጹሕ ፡ ስፍራ ፡ ትበላላችሁ ።
፲፭ የሚነሣውን ፡ ወርች ፡ የሚወዘወዘውንም ፡ ፍርምባ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለመወዝወዝ ፡ ቍርባን ፡ እንዲወዘውዙ ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ከሆነው ፡ ስብ ፡ ጋር ፡ ያመጣሉ ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘ ፡ ለአንተ ፡ ከአንተ ፡ ጋርም ፡ ለልጆችህ ፡ የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ይሆናል ።
፲፮ ሙሴም ፡ የኃጢአቱን ፡ መሥዋዕት ፡ ፍየል ፡ እጅግ ፡ ፈለገው ÷ እነሆም ፡ ተቃጥሎ ፡ ነበር ፤ ሙሴም ፡ የቀሩትን ፡ የአሮንን ፡ ልጆች ፡ አልዓዛር
፲፯ ንና ፡ ኢታምርን ፡ ተቈጥቶ ፡— ቅዱስ ፡ ቅዱሳን ፡ ነውና ÷ የሕዝቡንም ፡ ኃጢአት ፡ እንድትሸከሙ ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ እንድታስተሰርዩላቸው ፡ ለእናንተ ፡ ሰጥቶታልና ፡ ስለ ፡ ምን ፡ የኃጢአትን ፡ መሥዋዕት ፡ በቅዱሱ ፡
፲፰ ስፍራ ፡ አልበላችሁም ? እነሆ ፡ ደሙን ፡ ወደ ፡ መቅደሱ ፡ ውስጥ ፡ አላገባችሁትም ፤ እኔ ፡ እንዳዘዝሁ ፡ በቅዱሱ ፡ ስፍራ ፡ ውስጥ ፡ ትበሉት ፡
፲፱ ዘንድ ፡ ይገባችሁ ፡ ነበር ፡ አላቸው ። አሮንም ፡ ሙሴን ፡— እነሆ ፡ ዛሬ ፡ የኃጢአታቸውን ፡ መሥዋዕት ÷ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕታቸውን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አቀረቡ ፤ ይህም ፡ ሁሉ ፡ ደረሰብኝ ፤ ዛሬስ ፡ የኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ በበላሁ ፡ ኖሮ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ መልካም ፡
፳ ኖሮአልን ? አለው ። ሙሴም ፡ ሰማ ፡ በፊቱም ፡ መልካም ፡ ሆነ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ እን
፪ ዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ በሉአቸው ፡— ከምድር ፡ እንስሶች ፡ ሁሉ ፡ የምትበሉአቸው ፡ እነዚህ ፡
፫ ናቸው ። የተሰነጠቀ ፡ ሰኰና ፡ ያለውንና ፡ የሚ
፬ ያመሰኳውን ፡ እንስሳ ፡ ሁሉ ፡ ብሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ ከሚያመሰኩት ÷ ሰኰናቸውም ፡ ስንጥቅ ፡ ከሆነው ፡ ከእነዚህ ፡ አትበሉም ፤ ግመል ፡ ያመሰኳል ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ሰኰናው ፡ ስላልተሰነጠቀ ፡

፭፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ሽኮኮ ፡ ያመ
ሰኳል ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ሰኮናው ፡ ስላልተሰነጠቀ ፡
፮፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ጥንቸልም ፡
ያመሰኳል ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ሰኮናው ፡ ስላልተሰነ
፯፡ ጠቀ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። እርያም ፡
ሰኮናው ፡ ተሰንጥቆአል ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ስለማያ
፰፡ መሰኳ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። የእ
ነዚህን ፡ ሥጋ ፡ አትበሉም ፥ በድናቸውንም ፡
አትንኩም ፤ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ርኩሶች ፡ ናቸው ።

፱፡ በውኃ ፡ ውስጥ ፡ ከሚኖሩት ፡ ሁሉ ፡ እነዚ
ህን ፡ ትበላላችሁ ፤ በውኆች ፡ በባሕሮችም ፡
በወንዞችም ፡ ውስጥ ፡ ከሚኖሩት ፡ ሁሉ ፡ ክን
፲፡ ፍና ፡ ቅርፊት ፡ ያላቸውን ፡ ትበላላችሁ ። በው
ኆች ፡ ውስጥ ፡ ከሚንቀሳቀሱ ፥ በውኆች ፡
ውስጥ ፡ የሕይወት ፡ ነፍስ ፡ ካላቸው ፡ ሁሉ ፥
በባሕሮችና ፡ በወንዞች ፡ ውስጥ ፡ ክንፍና ፡ ቅር
ፊት ፡ የሌላቸው ፡ ሁሉ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ የተ
፲፩፡ ጸየፉ ፡ ናቸው ። በእናንተም ፡ ዘንድ ፡ የተጸ
የፉ ፡ ይሆናሉ ፤ ሥጋቸውንም ፡ አትበሉም ፥
፲፪፡ በድናቸውንም ፡ ትጸየፉላችሁ ። ክንፍና ፡ ቅር
ፊትም ፡ የሌላቸው ፡ በውኃ ፡ ውስጥ ፡ የሚኖ
ሩት ፡ ሁሉ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ የተጸየፉ ፡
ናቸው ።

፲፫፡ ከወፎችም ፡ ወገን ፡ የምትጸየፉአቸው ፡ እነ
ዚህ ፡ ናቸው ፤ አይበሉም ፤ የተጸየፉ ፡ ናቸው ፤
፲፬፡ ንስር ፥ ገዲ ፥ ዓሣ ፡ አውጭ ፥ ጭላት ፥ ጭል
፲፭፡ ፊት ፡ በየወገኑ ፥ ቍራ ፡ ሁሉ ፡ በየወገኑ ፥
፲፮፡ ሰጎን ፥ ጠላቋ ፥ ዝዪ ፥ በቋል ፡ በየወገኑ ፥
፲፯፡፲፰፡ ጕጕት ፥ እርኩም ፥ ጋጋኖ ፥ የውኃ ፡ ዶሮ ፥
፲፱፡ ይብራ ፥ ጥምብ ፡ አንሣ ፡ አሞራ ፥ ሽመላ ፥
ሳቢሳ ፡ በየወገኑ ፥ ጅንጁላቴ ፡ ወፍ ፥ የሌሊት ፡
ወፍ ።

፳፡ የሚበርርም ፥ በአራት ፡ እግሮችም ፡ የሚሄድ ፡
ተንቀሳቃሽ ፡ ሁሉ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ የተጸየፈ ፡
፳፩፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ ከሚበርሩት ፥ አራትም ፡
እግሮች ፡ ካሉአቸው ፥ ከእግሮቻቸውም ፡ በላይ ፡
በምድር ፡ ላይ ፡ የሚዘልሉባቸው ፡ ጭኖች ፡
ካሉአቸው ፡ ተንቀሳቃሾች ፡ እነዚህን ፡ ትበላላ
፳፪፡ ችሁ ። ከእነርሱም ፡ እነዚህን ፡ ትበላላችሁ ፤
አራቱን ፡ ዓይነት ፡ አንበጣዎች ፡ በየወገናቸው ።
፳፫፡ ነገር ፡ ግን ፡ የሚበርር ፥ አራትም ፡ እግሮች ፡
ያሉት ፡ ተንቀሳቃሽ ፡ ሁሉ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡
የተጸየፈ ፡ ነው ።

፳፬፡ በእነዚህም ፡ ርኩስ ፡ ትሆናላችሁ ፤ የእነር
ሱንም ፡ በድን ፡ የሚነካ ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡
፳፭፡ ርኩስ ፡ ነው ። ከእነርሱም ፡ በድን ፡ የሚያነሣ ፡
ሁሉ ፡ ልብሱን ፡ ይጠብ ፥ እስከ ፡ ማታም ፡
፳፮፡ ርኩስ ፡ ነው ። ሰኮናም ፡ ያለው ፥ ነገር ፡ ግን ፡
ሰኮናው ፡ ያልተሰነጠቀ ፥ የማያመሰኳም ፡ እን
ስሳ ፡ ሁሉ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤
፳፯፡ እርሱን ፡ የሚነካ ፡ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። በአ
ራት ፡ እግሮቹ ፡ ከሚሄድ ፡ እንስሳ ፡ ሁሉ ፡ በመ
ዳፎቹ ፡ ላይ ፡ የሚሄድ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ርኩስ ፡
ነው ፤ የእርሱን ፡ በድን ፡ የሚነካ ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡
፳፰፡ ማታ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። በድናቸውንም ፡ የሚያ
ነሣ ፡ ልብሱን ፡ ይጠብ ፥ እስከ ፡ ማታም ፡ ርኩስ ፡
ነው ። እነርሱም ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ርኩሶች ፡
ናቸው ።

፳፱፡ በምድር ፡ ላይም ፡ ከሚንቀሳቀስ ፡ ተንቀሳ
ቃሽ ፡ እነዚህ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ርኩሶች ፡
ናቸው ፤ ሙጭልጭላ ፥ አይጥ ፥ እንሽላሊት ፡
፴፡ በየወገኑ ፥ ኤሊ ፥ አዞ ፥ ገበሎ ፥ አርጃኖ ፥
፴፩፡ እስስት ። ከሚንቀሳቀሱት ፡ ሁሉ ፡ በእናንተ ፡
ዘንድ ፡ ርኩሶች ፡ የሚሆኑ ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።
ከእነርሱም ፡ የሞተውን ፡ የሚነካ ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡
፴፪፡ ማታ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ከእነርሱም ፡ የሞተው ፡
በምንም ፡ ላይ ፡ ቢወድቅ ፡ እርሱ ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤
የእንጨት ፡ ዕቃ ፡ ወይም ፡ ልብስ ፡ ወይም ፡ ቁር
በት ፡ ወይም ፡ ከረጢት ፡ ቢሆን ፡ የሚሠራበት ፡
ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ እርሱ ፡ በውኃ ፡ ውስጥ ፡ ይደረግ ፥
እስከ ፡ ማታም ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡
፴፫፡ ንጹሕ ፡ ይሆናል ። ከእነርሱም ፡ አንዳች ፡ በው
ስጡ ፡ የወደቀበትን ፡ የሸክላውን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡
ስበሩት ፥ በውስጡም ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡
፴፬፡ ነው ። በእርሱ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፥ ውኃም ፡
የሚፈስስበት ፥ የሚበላ ፡ መብል ፡ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡
ነው ፤ በዚህም ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ያለው ፡ የሚጠጣ ፡
፴፭፡ መጠጥ ፡ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ከእነዚህም ፡
በድን ፡ የሚወድቅበት ፡ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤
እቶን ፡ ወይም ፡ ምድጃ ፡ ቢሆን ፡ ይሰባበራል ፤
ርኩሶች ፡ ናቸው ፤ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ርኩሶች ፡
፴፮፡ ይሆናሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ ምንጩ ፥ ጕድጓዱም ፥
የውኃውም ፡ ኵሬ ፡ ንጹሐን ፡ ናቸው ፤ በድና
፴፯፡ ቸውን ፡ ግን ፡ የሚነካ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ከበድና
ቸውም ፡ በሚዘራ ፡ ዘር ፡ ላይ ፡ አንዳች ፡ ቢወ
፴፰፡ ድቅ ፡ እርሱ ፡ ንጹሕ ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ በዘሩ ፡
ላይ ፡ ውኃ ፡ ቢፈስስበት ፥ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከበድ
ናቸው ፡ አንዳች ፡ ቢወድቅበት ፥ በእናንተ ፡
ዘንድ ፡ ርኩስ ፡ ነው ።

፴፱፡ ለመብል ፡ ከሚሆኑላችሁ ፡ እንስሶች ፡ የሞተ ፡
ቢኖር ፥ በድኑን ፡ የሚነካ ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡
፵፡ ርኩስ ፡ ነው ። ከበድኑም ፡ የሚበላ ፡ ልብሱን ፡
ያጥባል ፥ እስከ ፡ ማታም ፡ ርኩስ ፡ ይሆናል ፤
በድኑንም ፡ የሚያነሣ ፡ ልብሱን ፡ ይጠብ ፥
እስከ ፡ ማታም ፡ ርኩስ ፡ ነው ።

፵፩፡ በምድርም ፡ ላይ ፡ የሚንቀሳቀስ ፡ ተንቀሳቃሽ ፡
፵፪፡ ሁሉ ፡ የተጸየፈ ፡ ነው ፥ አትብሉትም ። በሆዱ ፡
የሚሳብ ፥ በአራትም ፡ እግሮች ፡ የሚሳብ ፥ ብዙ ፡
እግሮችም ፡ ያሉት ፥ በምድርም ፡ ላይ ፡ የሚን
ቀሳቀሱ ፡ ተንቀሳቃሾች ፡ ሁሉ ፡ የተጸየፉ ፡ ናቸ
፵፫፡ ውና ፡ አትብሉአቸው ። በሚንቀሳቀሱ ፡ ተን
ቀሳቃሾች ፡ ሁሉ ፡ ሰውነታችሁን ፡ አታስጸይፉ ፤
በእነርሱም ፡ እንዳትረከሱ ፡ ሰውነታችሁን ፡ አታ
፵፬፡ ርክሱባቸው ። እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ
ችሁ ፡ ነኝና ፤ ሰውነታችሁን ፡ ቀድሱ ፥ ቅዱሳ
ንም ፡ ሁኑ ፥ እኔ ፡ ቅዱስ ፡ ነኝና ፤ በምድርም ፡
ላይ ፡ በሚሳብ ፡ ተንቀሳቃሽ ፡ ሁሉ ፡ ሰውነታች
፵፭፡ ሁን ፡ አታርክሱ ። እኔ ፡ አምላካችሁ ፡ እሆን ፡

ዘንድ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣኋችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ፤ እንግዲህ ፡ እኔ ፡ ቅዱስ ፡ ነኝና ፡ እናንተ ፡ ቅዱሳን ፡ ሁኑ ።

፵፮ የእንስሳና ፡ የወፍ ÷ በውኃም ፡ ውስጥ ፡ የሚንቀሳቀስ ፡ የፍጥረት ፡ ሁሉ ÷ በምድርም ፡ ላይ ፡ የሚንቀሳቀስ ፡ የፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ። ፵፯ በርኩስና ፡ በንጹሕ ፡ መካከል ÷ የሕይወት ፡ ነፍስ ፡ ከላቸውም ፡ በምትበሉትና ፡ በማትበሉት ፡ መካከል ፡ እንድትለዩ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ፪ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— ሴት ፡ ብታረግዝ ፡ ወንድ ፡ ልጅም ፡ ብትወልድ ÷ ሰባት ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ የረከሰች ፡ ናት ፤ እንደ ፡ ሕመምዋ ፡ መርገም ፡ ወራት ፡ ትረከሳለች ። ፫ በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ ልጁ ፡ ከሥጋው ፡ ሸለፈት ፡ ይገረዝ ። ፬ ከደምዋም ፡ እስክትነጻ ፡ ሠላሳ ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ትቀመጥ ፤ የመንጻትዋ ፡ ቀንም ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ የተቀደሰን ፡ ነገር ፡ አትንካ ÷ ወደ ፡ መቅደስም ፡ አትግባ ። ፭ ሴት ፡ ልጅም ፡ ብትወልድ ፡ እንደ ፡ መርገምዋ ፡ ወራት ፡ ሁለት ፡ ሳምንት ፡ ያህል ፡ የረከሰች ፡ ናት ፤ ከደምዋም ፡ እስክትነጻ ፡ ድረስ ፡ ስድሳ ፡ ስድስት ፡ ቀን ፡ ትቀመጥ ።

፮ የመንጻትዋ ፡ ወራትም ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ÷ ለወንድ ፡ ልጅ ፡ ወይም ፡ ለሴት ፡ ልጅ ÷ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ጠቦት ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ÷ የርግብም ፡ ግልገል ፡ ወይም ፡ ዋኖስ ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ታምጣለት ። ፯ እርሱም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያቀርበዋል ፡ ያስተሰርይላትማል ፤ ከደምዋም ፡ ፈሳሽ ፡ ትነጻለች ። ወንድ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ለምትወልድ ፡ ሴት ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ። ፰ ጠቦት ፡ ለማምጣት ፡ ገንዘብዋ ፡ ያልበቃት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሁለት ፡ ዋኖሶች ፡ ወይም ፡ ሁለት ፡ የርግብ ፡ ግልገሎች ÷ አንዱን ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ሌላውንም ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ታቀርባለች ፤ ካህኑም ፡ ያስተሰርይላታል ÷ እርስዋም ፡ ትነጻለች ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— ፪ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ በሥጋው ፡ ቁርበት ፡ ላይ ፡ እባጭ ፡ ወይም ፡ ብጉር ፡ ወይም ፡ ቋቁቻ ፡ ቢታይ ÷ በሥጋው ፡ ቁርበት ፡ እንደ ፡ ለምጽ ፡ ደዌ ፡ ቢመስል ÷ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ወደ ፡ አሮን ፡ ወይም ፡ ከካህናቱ ፡ ልጆቹ ፡ ወደ ፡ አንዱ ፡ ያምጡት ። ፫ ካህኑም ፡ በሥጋው ፡ ቁርበት ፡ ያለውን ፡ ደዌ ፡ ያያል ፤ ጠጕሩም ፡ ተለውጦ ፡ ቢነጣ ፡ ደዌውም ፡ ወደ ፡ ሥጋው ፡ ቁርበት ፡ ቢጠልቅ ÷ እርሱ ፡ የለምጽ ፡ ደዌ ፡ ነው ፤ ካህኑም ፡ አይቶ ፡— ርኩስ ፡ ነው ፡ ይበለው ። ፬ ቋቁቻውም ፡ በሥጋው ፡ ቁርበት ፡ ላይ ፡ ቢነጣ ÷ ከቁርበቱም ፡ የጠለቀ ፡ ባይመስል ÷ ጠጕሩም ፡ ባይነጣ ÷ ካህኑ ፡ የታመመውን ፡ ሰው ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ይዘጋበታል ። ፭ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ ካህኑ ፡ ያየዋል ፤ እነሆም ÷ ደዌው ፡ በዓይኑ ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ቢሆን ÷ በቁርበቱም ፡ ላይ ፡ ባይሰፋ ÷ ካህኑ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ደግሞ ፡ ይዘጋበታል ። ፮ ደግሞ ፡ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ካህኑ ፡ ያየዋል ፤ እነሆም ÷ ደዌው ፡ ቢከስም ÷ ደዌውም ፡ በቁርበቱ ፡ ላይ ፡ ባይሰፋ ÷ ካህኑ ፡— ንጹሕ ፡ ነው ፡ ይለዋል ፤ እከክ ፡ ነው ፤ ልብሱንም ፡ አጥቦ ፡ ንጹሕ ፡ ይሆናል ። ፯ ስለ ፡ መንጻቱ ፡ በካህኑ ፡ ዘንድ ፡ ከታየ ፡ በኋላ ፡ እከኩ ፡ በቁርበቱ ፡ ላይ ፡ ቢሰፋ ÷ እንደ ፡ ገና ፡ ሊታይ ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ይቀርባል ። ፰ ካህኑም ፡ ያያል ፤ እነሆም ÷ እከኩ ፡ በቁርበቱ ፡ ላይ ፡ ቢሰፋ ÷ ካህኑ ፡— ርኩስ ፡ ነው ፡ ይለዋል ፤ ለምጽ ፡ ነው ።

፱ የለምጽ ፡ ደዌ ፡ በሰው ፡ ውስጥ ፡ ቢሆን ፡ እርሱን ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ያመጡለታል ። ፲ ካህኑም ፡ ያያል ፤ እነሆም ÷ በቁርበቱ ፡ ላይ ፡ ነጭ ፡ እባጭ ፡ ቢሆን ÷ ጠጕሩም ፡ ተለውጦ ፡ ቢነጣ ÷ ሥጋውም ፡ በእባጩ ፡ ውስጥ ፡ ቢያዥ ÷ ፲፩ እርሱ ፡ በሥጋው ፡ ቁርበት ፡ ላይ ፡ አሮጌ ፡ ለምጽ ፡ ነው ÷ ካህኑም ፡— ርኩስ ፡ ነው ፡ ይለዋል ፤ እርሱ ፡ ርኩስ ፡ ነውና ፡ አይዘጋበትም ። ፲፪ ለምጹም ፡ በቁርበቱ ፡ ላይ ፡ ሰፍቶ ፡ ቢወጣ ÷ ለምጹም ፡ የታመመውን ፡ ሰው ፡ ቁርበቱን ፡ ሁሉ ፡ ከራሱ ፡ እስከ ፡ እግሮቹ ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ ከደነው ፡ ለካህኑ ፡ ቢመስለው ÷ ፲፫ ካህኑ ፡ ያያል ፤ እነሆም ÷ ለምጹ ፡ ሥጋውን ፡ ሁሉ ፡ ቢከድን ፡ የታመመውን ፡ ሰው ፡— ንጹሕ ፡ ነው ፡ ይለዋል ፤ ሥጋው ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሞ ፡ ተለውጦ ፡ ነጭ ፡ ሆኖአል ፤ ንጹሕ ፡ ነው ። ፲፬ የሚያዥው ፡ ሥጋ ፡ ግን ፡ ሲታይበት ፡ ርኩስ ፡ ይሆናል ። ፲፭ ካህኑም ፡ የሚያዥውን ፡ ሥጋ ፡ አይቶ ፡— ርኩስ ፡ ነው ፡ ይለዋል ፤ የሚያዥው ፡ ሥጋ ፡ ለምጽ ፡ ነውና ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ፲፮ የሚያዥውም ፡ ሥጋ ፡ ተለውጦ ፡ ቢነጣ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ይመጣል ። ፲፯ ካህኑም ፡ ያየዋል ፤ እነሆም ÷ ደዌው ፡ ቢነጣ ፡ ካህኑ ፡ የታመመውን ፡— ንጹሕ ፡ ነው ፡ ይለዋል ፤ ንጹሕ ፡ ነው ።

፲፰ በሥጋውም ፡ ቁርበት ፡ ላይ ፡ ቍስል ፡ ቢሆንና ፡ ቢሽር ÷ ፲፱ በቍስሉም ፡ ስፍራ ፡ ነጭ ፡ እባጭ ፡ ወይም ፡ ቀላ ፡ ያለ ፡ ቋቁቻ ፡ ቢወጣ ÷ በካህኑ ፡ ዘንድ ፡ ይታያል ። ፳ ካህኑም ፡ ያያል ፤ እነሆም ÷ ወደ ፡ ቁርበቱ ፡ ውስጥ ፡ ጠልቆ ፡ ቢታይ ÷ ጠጕሩም ፡ ተለውጦ ፡ ቢነጣ ÷ ካህኑ ፡— ርኩስ ፡ ነው ፡ ይለዋል ፤ የለምጽ ፡ ደዌ ፡ ነው ፤ ከቍስሉ ፡ ውስጥ ፡ ወጥቶአል ። ፳፩ ካህኑም ፡ ቢያየው ÷ ነጭም ፡ ጠጕር ፡ ባይኖርበት ÷ ወደ ፡ ቁርበቱም ፡ ውስጥ ፡ ባይጠልቅ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ቢከስም ÷ ካህኑ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ይዘጋበታል ። ፳፪ በቁርበቱም ፡ ላይ ፡ ቢሰፋ ÷ ካህኑ ፡— ርኩስ ፡ ነው ፡ ይለዋል ፤ ደዌ ፡ ነው ። ፳፫ ቋቁቻው ፡ ግን ፡ በስፍራው ፡ ቢቆም ፡ ባይሰፋም ÷ የቍስል ፡ ጠባሳ ፡ ነው ፤ ካህኑም ፡— ንጹሕ ፡ ነው ፡ ይለዋል ።

፳፬ ፡ በሥጋውም ፡ ቁርበት ፡ የእሳት ፡ ትኵሳት ፡
ቢኖርበት ÷ በተቃጠለውም ፡ ስፍራ ፡ ነጭ ፡
፳፭ ፡ ወይም ፡ ቀላ ፡ ያለ ፡ ቋቁቻ ፡ ቢታይ ÷ ካህኑ ፡
ያየዋል ፤ እነሆም ÷ በቋቁቻው ፡ ጠጕሩ ፡ ተለ
ውጦ ፡ ቢነጣ ÷ ወደ ፡ ቁርበቱም ፡ ውስጥ ፡ ቢጠ
ልቅ ÷ ለምጽ ፡ ነው ፤ ከተቃጠለውም ፡ ስፍራ ፡
ወጥቶአል ፤ ካህኑም ፡— ርኩስ ፡ ነው ፡ ይለዋል ፤
፳፮ ፡ የለምጽ ፡ ደዌ ፡ ነው ። ካህኑም ፡ ቢያየው ÷ በቋ
ቁቻውም ፡ ነጭ ፡ ጠጕር ፡ ባይኖር ÷ ወደ ፡ ቁር
በቱም ፡ ባይጠልቅ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ቢከስም ÷
፳፯ ፡ ካህኑ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ይዘጋበታል ። ካህኑም ፡
በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ያየዋል ፤ በቁርበቱም ፡ ላይ ፡
ቢሰፋ ፡ ካህኑ ፡— ርኩስ ፡ ነው ፡ ይለዋል ፤ የለ
፳፰ ፡ ምጽ ፡ ደዌ ፡ ነው ። ቋቁቻውም ፡ በስፍራው ፡
ላይ ፡ ቢቆም ÷ በቁርበቱም ፡ ላይ ፡ ባይሰፋ ፡ ነገር ፡
ግን ፡ ቢከስም ÷ የትኵሳት ፡ እባጭ ፡ ነው ፤ የት
ኵሳትም ፡ ጠባሳ ፡ ነውና ፡ ካህኑ ፡— ንጹሕ ፡
ነው ፡ ይለዋል ።

፳፱ ፡ ማናቸውም ፡ ወንድ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ በራሱ ፡
፴ ፡ ወይም ፡ በአገጩ ፡ ደዌ ፡ ቢኖርበት ÷ ካህኑ ፡
ደዌውን ፡ ያያል ፤ እነሆም ÷ ወደ ፡ ቁርበቱ ፡ ቢጠ
ልቅ ÷ በውስጡም ፡ ቀጭን ፡ ብጫ ፡ ጠጕር ፡ ቢኖ
ርበት ÷ ካህኑ ፡— ርኩስ ፡ ነው ፡ ይለዋል ፤ ቈረቈር ፡
ነው ፤ የራስ ፡ ወይም ፡ የአገጭ ፡ ለምጽ ፡ ነው ።
፴፩ ፡ ካህኑም ፡ የቈረቈሩን ፡ ደዌ ፡ ቢያይ ÷ ወደ ፡ ቁር
በቱም ፡ ባይጠልቅ ÷ ጥቁርም ፡ ጠጕር ፡ ባይኖ
ርበት ÷ ካህኑ ፡ የቈረቈር ፡ ደዌ ፡ ያለበትን ፡ ሰው ፡
፴፪ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ይዘጋበታል ። ካህኑም ፡ በሰባተ
ኛው ፡ ቀን ፡ ደዌውን ፡ ያያል ፤ እነሆም ÷ ቈረ
ቈሩ ፡ ባይሰፋ ÷ በውስጡም ፡ ብጫ ፡ ጠጕር ፡
ባይኖር ÷ የቈረቈሩም ፡ መልክ ፡ ወደ ፡ ቁርበቱ ፡
፴፫ ፡ ባይጠልቅ ÷ ይላጫል ÷ ቈረቈሩ ፡ ግን ፡ አይላ
ጭም ፤ ካህኑም ፡ ቈረቈር ፡ ያለበትን ፡ ሰው ፡
፴፬ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ደግሞ ፡ ይዘጋበታል ። ካህኑም ፡
በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ቈረቈሩን ፡ ያያል ፤ እነሆም ÷
ቈረቈሩ ፡ በቁርበቱ ፡ ላይ ፡ ባይሰፋ ÷ መልኩም ፡
ወደ ፡ ቁርበቱ ፡ ባይጠልቅ ÷ ካህኑ ፡— ንጹሕ ፡
ነው ፡ ይለዋል ፤ ልብሱን ፡ አጥቦ ፡ ንጹሕ ፡ ይሆ
፴፭ ፡ ናል ። ከነጻ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ቈረቈሩ ፡ በቁርበቱ ፡
፴፮ ፡ ላይ ፡ ቢሰፋ ÷ ካህኑ ፡ ያየዋል ፤ እነሆም ÷ ቈረ
ቈሩ ፡ በቁርበቱ ፡ ላይ ፡ ቢሰፋ ፡ ካህኑ ፡ ብጫ
ውን ፡ ጠጕር ፡ አይፈልግም ፤ ርኩስ ፡ ነው ።
፴፯ ፡ ቈረቈሩ ፡ ግን ፡ በዓይኑ ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡
ቢሆን ÷ ጥቁርም ፡ ጠጕር ፡ ቢበቅልበት ÷ ቈረ
ቈሩ ፡ ሽሮአል ፡ እርሱም ፡ ንጹሕ ፡ ነው ፤ ካህ
ኑም ፡— ንጹሕ ፡ ነው ፡ ይለዋል ።

፴፰ ፡ ማናቸውም ፡ ወንድ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ በሥጋው ፡
፴፱ ፡ ቁርበት ፡ ላይ ፡ ነጭ ፡ ቋቁቻ ፡ ቢኖርበት ÷ ካህኑ ፡
ያያል ፤ እነሆም ÷ በሥጋቸው ፡ ቁርበት ፡ ላይ ፡
ያለው ፡ ቋቁቻ ፡ ፈገግ ፡ ቢል ፡ አጓጕት ፡ ነው ፤
ከቁርበቱ ፡ ውስጥ ፡ ወጥቶአል ፤ ንጹሕ ፡ ነው ።
፵ ፡ የሰውም ፡ ጠጕር ፡ ከራሱ ፡ ቢመለጥ ፡ እርሱ ፡
፵፩ ፡ ቡሀ ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ንጹሕ ፡ ነው ። ጠጕ
ሩም ፡ ከግምባሩ ፡ ቢመለጥ ፡ እርሱ ፡ ራሰ ፡ በራ ፡
ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ንጹሕ ፡ ነው ። በቡሀነቱ ፡ ፵፪ ፡
ወይም ፡ በራሰ ፡ በራነቱ ፡ ነጭ ፡ ወይም ፡ ቀላ ፡
ያለ ፡ ደዌ ፡ ቢኖርበት ÷ እርሱ ፡ ከቡሀነቱ ፡
ወይም ፡ ከራሰ ፡ በራነቱ ፡ የወጣ ፡ ለምጽ ፡ ነው ።
፵፫ ፡ ካህኑም ፡ ያየዋል ፤ እነሆም ÷ የደዌው ፡ እብ
ጠት ÷ በሥጋው ፡ ቁርበት ፡ ላይ ፡ የሆነ ፡ ለምጽ ፡
መስሎ ÷ በቡሀነቱ ፡ ወይም ፡ በራሰ ፡ በራነቱ ፡
፵፬ ፡ ነጭ ፡ ወይም ፡ ቀላ ፡ ያለ ፡ ቢሆን ÷ ለምጻም ፡
ሰው ፡ ነው ፤ ርኩስ ፡ ነው ፤ ካህኑ ፡— በእርግጥ ፡
ርኩስ ፡ ነው ፡ ይለዋል ፤ ደዌው ፡ በራሱ ፡ ነው ።
፵፭ ፡ የለምጽ ፡ ደዌ ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ ልብሱ ፡ የተ
ቀደደ ፡ ይሁን ÷ ራሱም ፡ የተገለጠ ፡ ይሁን ÷ ከን
ፈሩንም ፡ ይሸፍን ፤ ርኩስ ፡ ርኩስ ፡ ነኝ ፡ ይበል ።
፵፮ ፡ ደዌው ፡ ባለበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡ ይሆ
ናል ፤ እርሱ ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤ ብቻውን ፡ ይቀ
መጣል ፤ መኖሪያውም ፡ ከሰፈር ፡ በውጭ ፡ ይሆ
ናል ።

፵፯ ፡ የለምጽም ፡ ደዌ ፡ በልብስ ፡ ላይ ፡ ቢሆን ÷
ልብሱም ፡ የበግ ፡ ጠጕር ፡ ወይም ፡ በፍታ ፡
፵፰ ፡ ቢሆን ÷ በድሩ ፡ ወይም ፡ በማጉ ፡ ላይ ፡ ቢሆን ÷
በፍታ ፡ ወይም ፡ የበግ ፡ ጠጕር ፡ ቢሆን ÷ አጐዛ ፡
ወይም ፡ ከአጐዛ ፡ የሚደረግ ፡ ነገር ፡ ቢሆን ÷
፵፱ ፡ ደዌው ፡ በልብሱ ፡ ወይም ፡ በአጐዛው ፡ ወይም ፡
በድሩ ፡ ወይም ፡ በማጉ ፡ ወይም ፡ ከአጐዛው ፡
በሚደረገው ፡ ነገር ፡ አረንጓዴ ፡ ወይም ፡ ቀይ ፡
ቢሆን ÷ የለምጽ ፡ ደዌ ፡ ነው ፤ ለካህኑ ፡ ይታ
፶ ፡ ያል ። ካህኑም ፡ ደዌውን ፡ አይቶ ፡ ደዌው ፡
ያለበትን ፡ ነገር ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ይዘጋበታል ።
፶፩ ፡ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ ደዌውን ፡ ያያል ፤ ደዌ
ውም ፡ በልብስ ፡ ላይ ፡ ወይም ፡ በድሩ ፡ ወይም ፡
በማጉ ፡ ወይም ፡ በአጐዛው ፡ ወይም ፡ ከአጐ
ዛው ፡ በሚደረግ ፡ ነገር ፡ ቢሰፋ ÷ ደዌው ፡ እየ
ፋገ ፡ የሚሄድ ፡ ለምጽ ፡ ነው ፤ ርኩስ ፡ ነው ።
፶፪ ፡ ልብሱን ፡ ያቃጥል ፤ ድሩ ፡ ወይም ፡ ማጉ ፡ የበግ ፡
ጠጕር ፡ ወይም ፡ በፍታ ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ከአ
ጐዛው ፡ የተደረገ ፡ ቢሆን ÷ ደዌ ፡ ያለበት ፡ ሁሉ ÷
እየፋገ ፡ የሚሄድ ፡ ለምጽ ፡ ነውና ፡ በእሳት ፡
ይቃጠል ።

፶፫ ፡ ካህኑ ፡ ቢያይ ÷ እነሆም ÷ ደዌው ፡ በድሩ ፡
ወይም ፡ በማጉ ፡ ወይም ፡ ከአጐዛ ፡ በተደረገ ፡
፶፬ ፡ ነገር ፡ ቢሆን ፡ በልብሱ ፡ ላይ ፡ ባይሰፋ ÷ ካህኑ ፡
ደዌ ፡ ያለበቱ ፡ ነገር ፡ እንዲታጠብ ፡ ይዘዝ ፤
፶፭ ፡ ሌላም ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ይዘጋበታል ። ደዌውም ፡
ከታጠበ ፡ በኋላ ፡ ካህኑ ፡ ያያል ፤ እነሆም ÷
ደዌው ፡ መልኩን ፡ ባይለውጥ ፡ ባይሰፋም ÷
ርኩስ ፡ ነው ፤ በእሳት ፡ አቃጥለው ፤ ምልክቱ ፡
በውስጥ ፡ ወይም ፡ በውጭ ፡ ቢሆን ፡ እየፋገ ፡
የሚሄድ ፡ ደዌ ፡ ነው ።

፶፮ ፡ ካህኑም ፡ ቢያይ ÷ እነሆም ÷ ደዌው ፡ ከታጠበ ፡
በኋላ ፡ ቢከስም ÷ ከልብሱ ፡ ወይም ፡ ከአጐዛው ፡
ወይም ፡ ከድሩ ፡ ወይም ፡ ከማጉ ፡ ይቅደደው ።
፶፯ ፡ በልብሱም ፡ ወይም ፡ በድሩ ፡ ወይም ፡ በማጉ ፡
ወይም ፡ ከአጐዛው ፡ በተደረገ ፡ ነገር ፡ ላይ ፡
ደግሞ ፡ ቢታይ ÷ የወጣ ፡ ለምጽ ፡ ነው ፤ ደዌው ፡

፶፰ ያለበትን ፡ ነገር ፡ አቃጥለው ። አንተም ፡ ከጠ
ብኸው ፡ ልብስ ፡ ወይም ፡ ከድሩ ፡ ወይም ፡
ከማጉ ፡ ወይም ፡ ከአጐዛው ፡ ከተደረገው ፡ ነገር ፡
ላይ ፡ ደዌው ፡ ቢጠፋ ÷ ሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡ ይታጠ
ባል ÷ ንጹሕም ፡ ይሆናል ።
፶፱ በበግ ፡ ጠጉር ፡ ልብስ ፡ ወይም ፡ በበፍታ ፡
ወይም ፡ በድሩ ፡ ወይም ፡ በማጉ ፡ ወይም ፡ ከአ
ጐዛ ፡ በተደረገ ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ ቢሆን ÷ ንጹሕ ፡
ወይም ፡ ርኩስ ፡ ያሰኝ ፡ ዘንድ ፡ የለምጽ ፡ ደዌ ፡
ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡
፪ ተናገረው ፡— በመንጻቱ ፡ ቀን ፡ የለምጻሙ ፡
ሕግ ፡ ይህ ፡ ይሆናል ፤ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ይወስዱ
፫ ታል ። ካህኑም ፡ ከሰፈር ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ይወ
ጣል ፤ ካህኑም ፡ ያያል ፤ እነሆም ÷ የለምጹ ፡
፬ ደዌ ፡ ከለምጻሙ ፡ ላይ ፡ ቢጠፋ ÷ ካህኑ ፡ ስለ
ሚነጻው ፡ ሰው ፡ ሁለት ፡ ንጹሐን ፡ ወፎች ፡
በሕይወታቸው ÷ የዝግባም ፡ እንጨት ÷ ቀይ ፡
ግምጃም ÷ ሂሶጵም ፡ ያመጣ ፡ ዘንድ ፡ ያዝዛል ።
፭ ካህኑም ፡ ከሁለቱ ፡ ወፎች ፡ አንዱን ፡ በሸክላ ፡
ዕቃ ፡ ውስጥ ፡ በምንጭ ፡ ውኃ ፡ ላይ ፡ ያርድ ፡
፮ ዘንድ ፡ ያዝዛል ። ሕያውንም ፡ ወፍ ፡ ዝግባው
ንም ፡ እንጨት ፡ ቀዩንም ፡ ግምጃ ፡ ሂሶጹንም ፡
ወስዶ ፡ ከሕያው ፡ ወፍ ፡ ጋር ፡ በምንጭ ፡ ውኃ ፡
ላይ ፡ በታረደው ፡ ወፍ ፡ ደም ፡ ውስጥ ፡ ይነከ
፯ ራቸዋል ። ከለምጹ ፡ በሚነጻው ፡ ሰው ፡ ላይ ፡
ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ይረጫል ፤ ንጹሕም ፡ ነው ፡ ይለ
ዋል ÷ ሕያውንም ፡ ወፍ ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡ ይለቅ
፰ ቀዋል ። የነጻውም ፡ ሰው ፡ ልብሱን ፡ ያጥባል ÷
ጠጉሩንም ፡ ሁሉ ፡ ይላጫል ÷ በውኃም ፡ ይታ
ጠባል ÷ ንጹሕም ፡ ይሆናል ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡
ወደ ፡ ሰፈር ፡ ይገባል ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ከድንኳኑ ፡
፱ በውጭ ፡ ሆኖ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ይቀመጣል ። በሰ
ባተኛውም ፡ ቀን ፡ ጠጉሩን ፡ ሁሉ ፡ ይላጫል ፤
ራሱንም ÷ ጢሙንም ÷ ቅንድቡንም ÷ የገላው
ንም ፡ ጠጉር ፡ ሁሉ ፡ ይላጫል ፤ ልብሱንም ÷
ገላውንም ፡ በውኃ ፡ ያጥባል ፤ ንጹሕም ፡ ይሆ
ናል ።
፲ በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ ነውር ፡ የሌለባቸ
ውን ፡ ሁለት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ÷ ነውር ፡ የሌለባት
ንም ፡ አንዲት ፡ የዓመት ፡ እንስት ፡ ጠቦት ÷ ስለ ፡
እህልም ፡ ቍርባን ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡
እጅ ፡ ሦስት ፡ እጅ ፡ የሆነ ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡
መልካም ፡ ዱቄት ÷ አንድ ፡ የሎግ ፡ መስፈሪ
፲፩ ያም ፡ ዘይት ፡ ይወስዳል ። የሚያነጻውም ፡
ካህን ፡ እነዚህን ፡ ነገሮች ፡ የሚነጻውንም ፡ ሰው ፡
በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ አጠገብ ፡ በእግ
፲፪ ዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያኖራቸዋል ። ካህኑም ፡ አን
ዱን ፡ ጠቦት ፡ ወስዶ ፡ ስለ ፡ በደል ፡ መሥዋዕት ፡
ያቀርበዋል ÷ ያንንም ፡ የሎግ ፡ መስፈሪያ ፡ ዘይት ፤
ስለ ፡ መወዝወዝ ፡ ቍርባን ፡ በእግዚአብሔር ፡
፲፫ ፊት ፡ ይወዘውዘዋል ። የኃጢአትን ፡ መሥዋ
ዕትና ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ በሚያር
ዱበት ፡ በተቀደሰው ፡ ስፍራ ፡ ጠቦቱን ፡ ያር
ደዋል ፤ የኃጢአቱ ፡ መሥዋዕት ፡ ለካህኑ ፡
እንደሚሆን ÷ እንዲሁ ፡ የበደል ፡ መሥዋዕት ፡
፲፬ ነው ፤ ቅዱስ ፡ ቅዱሳን ፡ ነው ። ካህኑም ፡ ከበ
ደል ፡ መሥዋዕት ፡ ደም ፡ ወስዶ ፡ የሚነጻውን ፡
ሰው ፡ የቀኝ ፡ ጆሮውን ፡ ጫፍ ÷ የቀኝ ፡ እጁ
ንም ፡ አውራ ፡ ጣት ÷ የቀኝ ፡ እግሩንም ፡ አውራ ፡
፲፭ ጣት ፡ ያስነካዋል ። ካህኑም ፡ ከዘይቱ ፡ ከሎግ ፡
መስፈሪያው ፡ ወስዶ ፡ በግራ ፡ እጁ ፡ ውስጥ ፡ ያፈ
፲፮ ስሰዋል ። ካህኑም ፡ በግራ ፡ እጁ ፡ ውስጥ ፡
ባለው ፡ ዘይት ፡ ቀኝ ፡ ጣቱን ፡ ነክሮ ፡ ከዘይቱ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ በጣቱ ፡
፲፯ ይረጫል ። ካህኑም ፡ በእጁ ፡ ውስጥ ፡ ከቀረው ፡
ዘይት ፡ የሚነጻውን ፡ ሰው ፡ የቀኝ ፡ ጆሮውን ፡
ጫፍ ÷ የቀኝ ፡ እጁንም ፡ አውራ ፡ ጣት ÷ የቀኝ ፡
እግሩንም ፡ አውራ ፡ ጣት ፡ የበደል ፡ መሥዋ
፲፰ ዕት ፡ ደም ፡ በረፈበት ፡ ላይ ፡ ያስነካዋል ። በካ
ህኑም ፡ እጅ ፡ ውስጥ ፡ የቀረውን ፡ ዘይት ፡ በሚ
ነጻው ፡ ሰው ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ያደርግበታል ፤ ካህ
ኑም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያስተሰርይለ
፲፱ ታል ። ካህኑም ፡ የኃጢአቱን ፡ መሥዋዕት ፡
ያቀርባል ÷ ከርኵሰቱም ፡ ለሚነጻው ፡ ሰው ፡
ያስተሰርይለታል ፤ በኋላም ፡ የሚቃጠለውን ፡
፳ መሥዋዕት ፡ ያርዳል ። ካህኑም ፡ የሚቃጠለ
ውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የእህሉን ፡ ቍርባን ፡
በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቀርባል ÷ ካህኑም ፡ ያስ
ተሰርይለታል ፤ እርሱም ፡ ንጹሕ ፡ ይሆናል ።
፳፩ ድሀም ፡ ቢሆን ፡ ይህንም ፡ ለማምጣት ፡ ገን
ዘቡ ፡ ባይበቃው ÷ ማስተስረያ ፡ ይሆንለት ፡ ዘንድ ፡
እንዲወዘወዝ ፡ አንድ ፡ ጠቦት ፡ ለበደል ፡ መሥ
ዋዕት ÷ ከመስፈሪያውም ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ አንድ ፡
እጅ ፡ የሆነ ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልካም ፡
ዱቄት ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ÷ አንድ ፡ የሎግ ፡ መስ
፳፪ ፈሪያም ፡ ዘይት ፡ ይወስዳል ። ሁለት ፡ ዋኖሶች ፡
ወይም ፡ የርግብ ፡ ግልገሎች ፡ እንደሚቻለው ÷
አንዱን ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ÷ ሌላውን ፡
፳፫ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ይወስዳል ። በስም
ንተኛውም ፡ ቀን ፡ ስለ ፡ መንጻት ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡
ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ በእግዚአ
፳፬ ብሔር ፡ ፊት ፡ ያመጣቸዋል ። ካህኑም ፡ የበደ
ሉን ፡ መሥዋዕት ፡ ጠቦት ፡ የሎግ ፡ መስፈሪያ
ውንም ፡ ዘይት ፡ ይወስዳል ፤ ካህኑም ፡ ለመወ
ዝወዝ ፡ ቍርባን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይወ
፳፭ ዘውዛቸዋል ። የበደሉንም ፡ መሥዋዕት ፡ ጠቦት ፡
ያርዳል ፤ ካህኑም ፡ ከበደሉ ፡ መሥዋዕት ፡ ደም ፡
ወስዶ ፡ የሚነጻውን ፡ ሰው ፡ የቀኝ ፡ ጆሮውን ፡
ጫፍ ÷ የቀኝ ፡ እጁንም ፡ አውራ ፡ ጣት ÷ የቀኝ ፡
፳፮ እግሩንም ፡ አውራ ፡ ጣት ፡ ያስነካዋል ። ካህኑም ፡
ከዘይቱ ፡ በግራ ፡ እጁ ፡ ውስጥ ፡ ያፈስሰዋል ።
፳፯ ካህኑም ፡ በግራ ፡ እጁ ፡ ውስጥ ፡ ካለው ፡ ዘይት ፡
በቀኝ ፡ ጣቱ ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአብሔር ፡
፳፰ ፊት ፡ ይረጨዋል ። ካህኑም ፡ በእጁ ፡ ውስጥ ፡
ካለው ፡ ዘይት ፡ የሚነጻውን ፡ ሰው ፡ የቀኝ ፡ ጆሮ

ውን ፡ ጫፍ ፥ የቀኝ ፡ እጁንም ፡ አውራ ፡ ጣት ፥
የቀኝ ፡ እግሩንም ፡ አውራ ፡ ጣት ፡ የበደል ፡
መሥዋዕት ፡ ደም ፡ በረፈበት ፡ ላይ ፡ ያስነካዋል ።
፳፱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያስተሰርይለት ፡ ዘንድ ፡
በካህኑ ፡ እጅ ፡ ውስጥ ፡ የቀረውን ፡ ዘይት ፡ በሚ
፴ ፡ ነጻው ፡ ሰው ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ያደርገዋል ። እንደ
ሚቻለው ፡ ከዋኖሶች ፡ ወይም ፡ ከርግብ ፡ ግልገ
፴፩ ፡ ሎች ፡ አንዱን ፡ ያቀርባል ። እንደሚቻለው ፡
አንዱን ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፥ ሌላውንም ፡
ከእህል ፡ ቍርባን ፡ ጋር ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ያቀርባል ፤ ካህኑም ፡ ለሚነጻው ፡ ሰው ፡
፴፪ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያስተሰርይለታል ። ለመ
ንጻቱ ፡ የሚያስፈልገውን ፡ ነገር ፡ ለማያገኝ ፡ የለ
ምጽ ፡ ደዌ ፡ ላለበት ፡ ሰው ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ።
፴፫ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ እን
፴፬ ፡ ዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— ወደምሰጣችሁ ፡
ርስት ፡ ወደ ፡ ከነዓን ፡ ምድር ፡ በገባችሁ ፡ ጊዜ ፥
እኔም ፡ የለምጽ ፡ ደዌ ፡ በርስታችሁ ፡ ምድር ፡
፴፭ ፡ በአንድ ፡ ቤት ፡ ባደረግሁ ፡ ጊዜ ፥ ባለቤቱ ፡
መጥቶ ፡ ካህኑን ፡— ደዌ ፡ በቤቴ ፡ ውስጥ ፡ እንዳለ ፡
፴፮ ፡ ይመስለኛል ፡ ብሎ ፡ ይንገረው ። ካህኑም ፡ በቤቱ ፡
ውስጥ ፡ ያለው ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ እንዳይረክስ ፥
እርሱ ፡ ደዌውን ፡ ለማየት ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ሳይገባ ፥
ቤቱን ፡ ባዶ ፡ እንዲያደርጉት ፡ ያዝዛል ፤ በኋላም ፡
፴፯ ፡ ካህኑ ፡ ቤቱን ፡ ለማየት ፡ ይገባል ። ደዌውንም ፡
ያያል ፤ እነሆም ፥ ደዌው ፡ በግንቡ ፡ ላይ ፡ በአረ
ንጓዴና ፡ በቀይ ፡ ቢዥጐረጐር ፥ መልኩም ፡
፴፰ ፡ ወደ ፡ ግንቡ ፡ ውስጥ ፡ ቢጠልቅ ፥ ካህኑ ፡ ከቤቱ ፡
ውስጥ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ በር ፡ ወጥቶ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡
፴፱ ፡ ቤቱን ፡ ይዘጋዋል ። ካህኑም ፡ በሰባተኛው ፡
ቀን ፡ ተመልሶ ፡ ያያል ፤ እነሆም ፥ ደዌው ፡ በቤቱ ፡
፵ ፡ ግንብ ፡ ላይ ፡ ቢሰፋ ፥ ካህኑ ፡ ደዌ ፡ ያለባቸውን ፡
ድንጋዮች ፡ እንዲያወጡ ፥ ከከተማውም ፡ ወደ ፡
ውጭ ፡ ወደ ፡ ረከሰው ፡ ስፍራ ፡ እንዲጥሉአ
፵፩ ፡ ቸው ፡ ያዝዛል ። ቤቱንም ፡ በውስጡ ፡ በዙሪ
ያው ፡ ያስፍቀዋል ፤ የፋቁትንም ፡ የምርጊቱን ፡
አፈር ፡ ከከተማው ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ወደ ፡ ረከሰ ፡
፵፪ ፡ ስፍራ ፡ ያፈስሱታል ። በእነዚያም ፡ ድንጋዮች ፡
ስፍራ ፡ ሌሎች ፡ ድንጋዮች ፡ ያገባሉ ፤ ሌላም ፡
ጭቃ ፡ ወስደው ፡ ቤቱን ፡ ይመርጉታል ።
፵፫ ፡ ደዌውም ፡ ዳግም ፡ ቢመለስ ፥ ድንጋዮቹም ፡
ከወጡ ፡ ቤቱም ፡ ከተፋቀና ፡ ከተመረገ ፡ በኋላ ፡
፵፬ ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ቢሰፋ ፥ ካህኑ ፡ ገብቶ ፡ ያያል ፤
እነሆም ፥ ደዌው ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ቢሰፋ ፥
በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፡ እየፋገ ፡ የሚሄድ ፡
፵፭ ፡ ለምጽ ፡ ነው ፤ ርኩስ ፡ ነው ። ቤቱንም ፥ ድንጋ
ዮቹንም ፥ እንጨቱንም ፥ የቤቱንም ፡ ምርጊት ፡
ሁሉ ፡ ያፈርሳል ፤ እነርሱንም ፡ ከከተማው ፡ ወደ ፡
፵፮ ፡ ውጭ ፡ ወደ ፡ ርኩስ ፡ ስፍራ ፡ ያወጣል ። በተዘ
ጋበትም ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ የሚገባ ፡
፵፯ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡ ይሆናል ። በቤ
ቱም ፡ የሚተኛ ፡ ልብሱን ፡ ያጥባል ፤ በቤቱም ፡
የሚበላ ፡ ልብሱን ፡ ያጥባል ።
፵፰ ፡ ካህኑም ፡ ገብቶ ፡ ቢያይ ፥ እነሆም ፥ ቤቱ ፡
ከተመረገ ፡ በኋላ ፡ ደዌው ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ባይ
ሰፋ ፥ ደዌው ፡ ስለ ፡ ሻረ ፡ ካህኑ ፡ ቤቱን ፡—
፵፱ ፡ ንጹሕ ፡ ነው ፡ ይለዋል ። ቤቱንም ፡ ለማንጻት ፡
ሁለት ፡ ወፎች ፥ የዝግባም ፡ እንጨት ፥ ቀይ ፡
፶ ፡ ግምጃም ፥ ሂሶጵም ፡ ይወስዳል ። አንደኛው
ንም ፡ ወፍ ፡ በሸክላ ፡ ዕቃ ፡ ውስጥ ፡ ከምንጭ ፡
፶፩ ፡ ውኃ ፡ በላይ ፡ ያርዳል ። የዝግባውን ፡ እንጨት ፥
ሂሶጱንም ፥ ቀዩንም ፡ ግምጃ ፥ ሕያውንም ፡ ወፍ ፡
ወስዶ ፡ በታረደው ፡ ወፍ ፡ ደምና ፡ በምንጭ ፡
ውኃ ፡ ውስጥ ፡ ይነክራቸዋል ፥ ቤቱንም ፡ ሰባት ፡
፶፪ ፡ ጊዜ ፡ ይረጨዋል ። ቤቱንም ፡ በወፉ ፡ ደም ፡ በም
ንጩም ፡ ውኃ ፡ በሕያውም ፡ ወፍ ፡ በዝግባ
ውም ፡ እንጨት ፡ በሂሶጱም ፡ በቀዩም ፡ ግምጃ ፡
፶፫ ፡ ያነጻዋል ። ሕያውንም ፡ ወፍ ፡ ከከተማ ፡ ወደ ፡
ሜዳ ፡ ይሰድደዋል ፤ ለቤቱም ፡ ያስተሰርይለ
ታል ፥ ንጹሕም ፡ ይሆናል ።
፶፬ ፡ ይህም ፡ ሕግ ፡ ነው ፡ ለሁሉ ፡ ዓይነት ፡ ለምጽ ፡
፶፭ ፡ ደዌ ፥ ለቈረቈርም ፥ በልብስና ፡ በቤትም ፡ ላለ ፡
፶፮ ፡ ለምጽ ፥ ለእብጥም ፥ ለብጕርም ፥ ለቋቁቻም ፤
፶፯ ፡ በሚረክስና ፡ በሚነጻ ፡ ጊዜ ፡ እንዲያስታውቅ ፡
ይህ ፡ የለምጽ ፡ ሕግ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ እን
፪ ፡ ዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— ለእስራኤል ፡
ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብላችሁ ፡ ንገሩአቸው ፡—
ማንም ፡ ሰው ፡ ከሥጋው ፡ ፈሳሽ ፡ ነገር ፡ ቢወጣ ፥
፫ ፡ ስለሚፈስሰው ፡ ነገር ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ስለሚፈ
ስሰው ፡ ነገር ፡ ርኵስነቱ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ፈሳሹ ፡
ነገር ፡ ከሥጋው ፡ ቢፈስስ ፡ ወይም ፡ ከመፍሰሱ ፡
፬ ፡ ቢቆም ፥ ርኩስ ፡ መሆኑ ፡ ነው ። ፈሳሽ ፡ ነገር ፡
ያለበት ፡ ሰው ፡ የሚተኛበት ፡ መኝታ ፡ ሁሉ ፡
ርኩስ ፡ ነው ፤ የሚቀመጥበትም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡
፭ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። መኝታውንም ፡ የሚነካ ፡ ሁሉ ፡
ልብሱን ፡ ይጠብ ፥ በውኃም ፡ ይታጠብ ፥ እስከ ፡
፮ ፡ ማታም ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ፈሳሽ ፡ ነገር ፡
ያለበት ፡ ሰው ፡ በተቀመጠበት ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ የሚ
ቀመጥበት ፡ ሰው ፡ ልብሱን ፡ ይጠብ ፥ በው
ኃም ፡ ይታጠብ ፥ እስከ ፡ ማታም ፡ ድረስ ፡
፯ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ፈሳሽ ፡ ነገር ፡ ያለበትን ፡ የሰ
ውን ፡ ሥጋ ፡ የሚነካ ፡ ልብሱን ፡ ይጠብ ፥ በው
ኃም ፡ ይታጠብ ፥ እስከ ፡ ማታም ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡
፰ ፡ ነው ። ፈሳሽ ፡ ነገር ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ በንጹሕ ፡
ሰው ፡ ላይ ፡ ቢተፋ ፥ ልብሱን ፡ ይጠብ ፥ በው
ኃም ፡ ይታጠብ ፥ እስከ ፡ ማታም ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡
፱ ፡ ነው ። ፈሳሽ ፡ ነገር ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ የተቀመ
፲ ፡ ጠበት ፡ ኮርቻ ፡ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ከበታ
ቹም ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ የሚነካ ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡
ማታ ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤ እነዚህንም ፡ ነገ
ሮች ፡ የሚያነሣ ፡ ልብሱን ፡ ይጠብ ፥ በውኃም ፡
ይታጠብ ፥ እስከ ፡ ማታም ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡
፲፩ ፡ ነው ። ፈሳሽ ፡ ነገር ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ እጁን ፡
በውኃ ፡ ሳይታጠብ ፡ የሚነካው ፡ ሁሉ ፡ ልብ
ሱን ፡ ይጠብ ፥ በውኃም ፡ ይታጠብ ፥ እስከ ፡

፲፪ ማታም ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ፈሳሽ ፡ ነገር ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ የሚነካውን ፡ የሸክላ ፡ ዕቃ ፡ ይሰበሩት ፤ የእንጨቱም ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ በውኃ ፡ ይታጠብ ።

፲፫ ፈሳሽ ፡ ነገር ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ ከፈሳሹ ፡ ነገር ፡ ሲነጻ ፡ ስለ ፡ መንጻቱ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ይቈጥራል ፤ ልብሱንም ፡ ያጥባል ÷ ገላውንም ፡ በምንጭ ፡ ፲፬ ውኃ ፡ ይታጠባል ÷ ንጹሕም ፡ ይሆናል ። በስ ምንተኛውም ፡ ቀን ፡ ሁለት ፡ ዋኖሶች ፡ ወይም ፡ ሁለት ፡ የርግብ ፡ ግልገሎች ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ መገ ናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይመጣል ÷ ለካህኑም ፡ ይሰጣቸዋል ። ፲፭ ካህኑም ፡ አንደኛውን ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋ ዕት ÷ ሌላውንም ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርባል ፤ ካህኑም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ስለ ፡ ፈሳሹ ፡ ነገር ፡ ያስተሰርይለታል ።

፲፮ የማንም ፡ ሰው ፡ ዘር ፡ ከእርሱ ፡ ቢወጣ ÷ ገላ ውን ፡ ሁሉ ፡ በውኃ ፡ ይታጠባል ÷ እስከ ፡ ማታም ፡ ፲፯ ርኩስ ፡ ነው ። ዘር ፡ የነካው ፡ ልብስ ፡ ሁሉ ፡ ቁር በትም ፡ ሁሉ ፡ በውኃ ፡ ይታጠባል ÷ እስከ ፡ ፲፰ ማታም ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ወንዱ ፡ በሴ ቲቱ ፡ ቢደርስባት ፡ ሁለቱ ፡ በውኃ ፡ ይታጠባሉ ÷ እስከ ፡ ማታም ፡ ድረስ ፡ ርኩሶች ፡ ናቸው ።

፲፱ ሴት ፡ ፈሳሽ ፡ ነገር ፡ ቢኖርባት ፡ በሥጋዋም ፡ ያለው ፡ ፈሳሽ ፡ ነገር ፡ ደም ፡ ቢሆን ÷ በመርገ ምዋ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ትቀመጣለች ፤ የሚነካ ትም ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ፳ መርገምም ፡ ስትሆን ፡ የምትተኛበት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤ የምትቀመጥበትም ፡ ነገር ፡ ፳፩ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። መኝታዋንም ፡ የሚነካ ፡ ሁሉ ፡ ልብሱን ፡ ያጥባል ÷ በውኃም ፡ ይታጠ ባል ÷ እስከ ፡ ማታም ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ፳፪ የምትቀመጥበትንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ የሚነካ ፡ ሁሉ ፡ ልብሱን ፡ ያጥባል ÷ በውኃም ፡ ይታጠ ፳፫ ባል ÷ እስከ ፡ ማታም ፡ ርኩስ ፡ ነው ። በመኝ ታዋም ፡ ላይ ፡ ወይም ፡ በምትቀመጥበት ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ ቢሆን ፡ ሲነካው ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ ፳፬ ርኩስ ፡ ነው ። ማንም ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ ቢተኛ ፡ መርገምዋም ፡ ቢነካው ÷ ሰባት ፡ ቀን ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤ የሚተኛበትም ፡ መኝታ ፡ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡ ነው ።

፳፭ ሴትም ፡ ከመርገም ፡ ቀን ፡ ሌላ ፡ ደምዋ ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ ቢፈስስ ÷ ወይም ፡ ደምዋ ፡ ከመርገምዋ ፡ ወራት ፡ የሚበልጥ ፡ ቢፈስስ ÷ በመርገምዋ ፡ ወራት ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ እንዲሁ ፡ በፈሳሽዋ ፡ ርኵስነት ፡ ወራት ፡ ትሆናለች ፤ ርኩስ ፡ ናት ። ፳፮ ደምዋም ፡ በሚፈስስበት ፡ ወራት ፡ ሁሉ ፡ የምት ተኛበት ፡ መኝታ ፡ ሁሉ ፡ በመርገምዋ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡ መኝታ ፡ ያለ ፡ ይሆንባታል ፤ የምትቀመጥበት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ መርገ ፳፯ ምዋ ፡ ርኵስነት ፡ ርኩስ ፡ ነው ። እነዚህንም ፡ ነገሮች ፡ የሚነካ ፡ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤ ልብሱ ንም ፡ ያጥባል ÷ በውኃም ፡ ይታጠባል ÷ እስከ ፡ ፳፰ ማታም ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ከፈሳሽዋም ፡ ብትነጻ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ትቈጥራለች ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ንጹሕ ፡ ትሆናለች ። ፳፱ በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ ሁለት ፡ ዋኖሶች ፡ ወይም ፡ ሁለት ፡ የርግብ ፡ ግል ገሎች ፡ ይዛ ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ታመጣቸዋለች ። ፴ ካህኑም ፡ አንደኛውን ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ÷ ሌላው ንም ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርባል ፤ ካህኑም ፡ ስለ ፡ ፈሳሽዋ ፡ ርኵስነት ፡ በእግዚአ ብሔር ፡ ፊት ፡ ያስተሰርይላታል ።

፴፩ እንዲሁም ፡ በእነርሱ ፡ መካከል ፡ ያለችውን ፡ ማደሪያዬን ፡ ባረከሱ ፡ ጊዜ ÷ በርኵስነታቸው ፡ እንዳይሞቱ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ከርኵስነ ታቸው ፡ ለያቸው ።

፴፪ ፈሳሽ ፡ ነገር ፡ ላለበት ፡ ሰው ÷ ይረክስም ፡ ፴፫ ዘንድ ፡ ዘሩ ፡ ለሚወጣበት ፡ ሰው ÷ በመርገም ዋም ፡ ለታመመች ÷ ፈሳሽም ፡ ነገር ፡ ላለባቸው ፡ ለወንድም ፡ ለሴትም ÷ የረከሰችንም ፡ ሴት ፡ ለሚገናኝ ፡ ሰው ፡ ሕጉ ፡ ይኸው ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የቀረቡና ፡ የሞቱ ፡ ሁለቱ ፡ የአሮን ፡ ልጆች ፡ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ እግዚአ ብሔር ፡ ሙሴን ፡ ተናገረው ፤ ፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— እኔ ፡ በስርየቱ ፡ መክደኛ ፡ ላይ ፡ በደመናው ፡ ውስጥ ፡ እታያለሁና ፡ እንዳ ይሞት ፡ በመጋረጃው ፡ ውስጥ ፡ በታቦቱ ፡ ላይ ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ ስርየቱ ፡ መክደኛ ፡ ወደ ፡ ተቀ ደሰው ፡ ስፍራ ፡ ሁልጊዜ ፡ እንዳይገባ ፡ ለወን ድምህ ፡ ለአሮን ፡ ንገረው ። ፫ እንዲሁ ፡ አሮን ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ወይፈን ÷ ለሚቃ ጠል ፡ መሥዋዕትም ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ተቀደሰ ፡ ስፍራ ፡ ይግባ ። ፬ የተቀደሰ ውን ፡ የበፍታ ፡ ቀሚስ ፡ ይልበስ ÷ የበፍታ ውም ፡ ሱሪ ፡ በገላው ፡ ላይ ፡ ይሁን ÷ የበፍ ታውንም መታጠቂያ ፡ ይታጠቅ ÷ የበፍታ ውንም ፡ መጠምጠሚያ ፡ ይጠምጥም ፤ እነ ዚህ ፡ የተቀደሱ ፡ ልብሶች ፡ ናቸው ፤ ገላው ንም ፡ በውኃ ፡ ታጥቦ ፡ ይልበሳቸው ። ፭ ከእስራ ኤልም ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ለኃጢአት ፡ መሥ ዋዕት ፡ ሁለት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ÷ ለሚቃጠ ልም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ይው ሰድ ።

፮ አሮንም ፡ ለእርሱ ፡ ያለውን ፡ የኃጢአቱን ፡ መሥዋዕት ፡ ወይፈን ፡ ያቀርባል ÷ ለራሱም ፡ ለቤተ ፡ ሰቡም ፡ ያስተሰርያል ። ፯ ሁለቱንም ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፡ ወስዶ ፡ በመገናኛው ፡ ድን ኳን ፡ ደጃፍ ፡ አጠገብ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያቆማቸዋል ። ፰ አሮንም ፡ በሁለቱ ፡ ፍየሎች ፡ ላይ ፡ ዕጣ ፡ ይጥልባቸዋል ÷ አንዱን ፡ ዕጣ ፡ ለእ ግዚአብሔር ፡ ሌላውንም ፡ ዕጣ ፡ ለሚለቀቅ ። ፱ አሮንም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ዕጣ ፡ የሆነበትን ፡ ፍየል ፡ ያቀርባል ÷ ስለ ፡ ኃጢአትም ፡ መሥዋ ዕት ፡ ያደርገዋል ። ፲ የመለቀቅም ፡ ዕጣ ፡ የሆነበ ትን ፡ ፍየል ፡ ያስተሰርይበት ፡ ዘንድ ÷ ለመለቀ ቅም ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ይሰድደው ፡ ዘንድ ፡

በሕይወቱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያቆመዋል ።

፲፩ አሮንም ፡ ስለ ፡ ራሱ ፡ ኃጢአት ፡ የሚሠዋውን ፡ መሥዋዕት ፡ ወይፈኑን ፡ ያቀርባል ፤ ለራሱም ፡ ለቤተ ፡ ሰቡም ፡ ያስተሰርያል ፤ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ የእርሱን ፡ መሥዋዕት ፡ ወይፈኑን ፡ ያርዳል ። ፲፪ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ካለው ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ የእሳት ፡ ፍም ፡ አምጥቶ ፡ ጥናውን ፡ ይሞላል ፥ ከተወቀጠውም ፡ ከጣፋጭ ፡ ዕጣን ፡ እጁን ፡ ሙሉን ፡ ይወስዳል ፤ ወደ ፡ መጋረጃውም ፡ ውስጥ ፡ ያመጣዋል ። ፲፫ እንዳይሞትም ፡ የጢሱ ፡ ደመና ፡ በምስክሩ ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ መክደኛ ፡ ይሸፍን ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ዕጣኑን ፡ በእሳቱ ፡ ላይ ፡ ያደርጋል ። ፲፬ ከወይፈኑም ፡ ደም ፡ ወስዶ ፡ በስርየቱ ፡ መክደኛ ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ በጣቱ ፡ ይረጨዋል ፤ ከደሙም ፡ በመክደኛው ፡ ፊት ፡ በጣቱ ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ይረጫል ።

፲፭ ስለ ፡ ሕዝቡም ፡ ኃጢአት ፡ የሚሠዋውን ፡ መሥዋዕት ፡ ፍየል ፡ ያርዳል ፥ ደሙንም ፡ ወደ ፡ መጋረጃው ፡ ውስጥ ፡ ያመጣዋል ፤ በወይፈኑም ፡ ደም ፡ እንዳደረገ ፡ በፍየሉ ፡ ደም ፡ ያደርጋል ፤ በመክደኛውም ፡ ላይና ፡ በመክደኛውም ፡ ፊት ፡ ይረጨዋል ። ፲፮ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ርኵስነት ፡ ከመተላለፋቸውም ፡ ከኃጢአታቸውም ፡ የተነሣ ፡ ለመቅደሱ ፡ ያስተሰርይለታል ፤ እንዲሁም ፡ በርኵስነታቸው ፡ መካከል ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ለኖረች ፡ ለመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ያደርጋል ። ፲፯ እርሱም ፡ ለማስተስረይ ፡ ወደ ፡ መቅደሱ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ለራሱ ፥ ለቤተ ፡ ሰቡም ፥ ለእስራኤል ፡ ጉባዔ ፡ ሁሉ ፡ አስተስርዮ ፡ እስኪወጣ ፡ ድረስ ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ማንም ፡ አይኖርም ። ፲፰ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ መሠዊያ ፡ ወጥቶ ፡ ያስተሰርይለታል ፤ ከወይፈኑም ፡ ደም ፡ ከፍየሉም ፡ ደም ፡ ወስዶ ፡ በመሠዊያው ፡ ዙሪያ ፡ ያሉትን ፡ ቀንዶች ፡ ያስነካል ። ፲፱ ከደሙም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ በጣቱ ፡ ይረጫል ፥ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ርኵስነት ፡ ያነጻዋል ፥ ይቀድሰውማል ።

፳ መቅደሱንም ፥ የመገናኛውንም ፡ ድንኳን ፥ መሠዊያውንም ፡ ማስተስረይ ፡ ከፈጸመ ፡ በኋላ ፡ ሕያውን ፡ ፍየል ፡ ያቀርባል ፤ ፳፩ አሮንም ፡ ሁለቱን ፡ እጆቹን ፡ በሕያው ፡ ፍየል ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይጭናል ፥ በላዩም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ በደል ፡ ሁሉ ፡ መተላለፋቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአታቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ይናዘዛል ፤ በፍየሉም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ያሸክመዋል ፥ በተዘጋጀው ፡ ሰውም ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ይሰድደዋል ። ፳፪ ፍየሉም ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ በረሀ ፡ ይሸከማል ፡ ፍየሉንም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ውስጥ ፡ ይለቅቀዋል ።

፳፫ አሮንም ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ይገባል ፥ ወደ ፡ መቅደሱም ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ የለበሰውን ፡ የበፍታ ፡ ልብስ ፡ ያወልቃል ፥ በዚያም ፡ ይተወዋል ፤ ፳፬ በተቀደሰውም ፡ ስፍራ ፡ ገላውን ፡ በውኃ ፡ ይታጠባል ፥ ሌላውንም ፡ ልብስ ፡ ለብሶ ፡ ይወጣል ፤ የእርሱንም ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፥ የሕዝቡንም ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርባል ፥ ለራሱም ፡ ለሕዝቡም ፡ ያስተሰርያል ። ፳፭ የኃጢአቱንም ፡ መሥዋዕት ፡ ስብ ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ። ፳፮ ለመለቀቅ ፡ የሚሆነውን ፡ ፍየል ፡ የወሰደ ፡ ሰው ፡ ልብሱን ፡ ያጥባል ፥ ገላውንም ፡ በውኃ ፡ ይታጠባል ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ ይገባል ። ፳፯ ለማስተስረያም ፡ እንዲሆን ፡ ደማቸው ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ የገባውን ፡ የኃጢአቱን ፡ መሥዋዕት ፡ ወይፈንና ፡ የኃጢአቱን ፡ መሥዋዕት ፡ ፍየል ፡ ከሰፈሩ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ያወጡአቸዋል ፤ ቁርበታቸውንም ፥ ሥጋቸውንም ፥ ፈርሳቸውንም ፡ በእሳት ፡ ያቃጥላሉ ። ፳፰ ያቃጠላቸውም ፡ ሰው ፡ ልብሱን ፡ ያጥባል ፥ ገላውንም ፡ በውኃ ፡ ይታጠባል ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሰፈር ፡ ይገባል ።

፳፱ ይህም ፡ የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ይሁንላችሁ ፤ ፴ በዚህ ፡ ቀን ፡ ትነጹ ፡ ዘንድ ፡ ማስተስረያ ፡ ይሆንላችኋልና ፡ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአሥረኛው ፡ ቀን ፡ ራሳችሁን ፡ አስጨንቁት ፥ የአገር ፡ ልጅም ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡ የተቀመጠም ፡ እንግዳ ፡ ሥራን ፡ ሁሉ ፡ አትሥሩበት ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ከኃጢአታችሁ ፡ ሁሉ ፡ ትነጻላችሁ ። ፴፩ ታላቅ ፡ ሰንበት ፡ ይሆንላችኋል ፥ ራሳችሁንም ፡ ታዋርዳላችሁ ፤ የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ነው ። ፴፪ የሚቀበውም ፥ በአባቱም ፡ ፋንታ ፡ ካህን ፡ ሊሆን ፡ የሚከነው ፡ ካህን ፡ ያስተስርይ ፥ የተቀደሰውንም ፡ የበፍታ ፡ ልብስ ፡ ይልበስ ፤ ፴፫ ለቅድስተ ፡ ቅዱሳንም ፡ ያስተሰርይ ፤ ለመገናኛውም ፡ ድንኳን ፡ ለመሠዊያውም ፡ ያስተስርይ ፤ ለካህናቱም ፡ ለጉባኤውም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ያስተሰርይ ። ፴፬ ይህም ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ በዓመት ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ስለ ፡ ኃጢአታቸው ፡ ሁሉ ፡ ያስተሰርይ ፡ ዘንድ ፡ የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ይሁንላችሁ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ፪ ለአሮንና ፡ ለልጆቹ ፡ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገር ፡— እግዚአብሔር ፡ ያዘዘው ፡ ይህ ፡ ነው ፥ እንዲህም ፡ አለ ፡— ፫ ከእስራኤል ፡ ቤት ፡ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ በሬ ፡ ወይም ፡ በግ ፡ ወይም ፡ ፍየል ፡ ቢያርድ ፥ በሰፈሩ ፡ ውስጥ ፡ ወይም ፡ ከሰፈሩ ፡ ውጭ ፡ ቢያርደው ፥ ፬ በእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ፊት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቍርባን ፡ ያቀርብ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ባያመጣው ፥ ደሙ ፡ በዚያ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ይቈጠርበታል ፤ ደም ፡ አፍስሶአል ፤ ያም ፡ ከሕዝቡ ፡ ተለይቶ ፡ ይጥፋ ። ፭ ስለዚህ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በሜዳ ፡ የሚያርዱትን ፡ መሥዋዕታቸውን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡

ያመጡታል ፤ ወደ ፡ ካህኑም ፡ አምጥተው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዉታል ። ፮ ካህኑም ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ባለው ፡ በእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ ደሙን ፡ ይረጨዋል ፥ ስቡንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ ያቃጥለዋል ። ፯ መሥዋዕታቸውንም ፡ ደግሞ ፡ ተከትለው ፡ ላመነዘሩባቸው ፡ ለሰይጣናት ፡ አይሠዉ ። ይህ ፡ ለእነርሱ ፡ ለልጅ ፡ ልጃቸው ፡ ለዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ይሁን ።

፰ ለእነርሱም ፡ እንዲህ ፡ በላቸው ፡— ከእስራኤል ፡ ቤት ፡ በመካከላቸውም ፡ ከሚኖሩ ፡ እንግዶች ፡ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ወይም ፡ ሌላ ፡ መሥዋዕት ፡ ቢያቀርብ ፥ ፱ ለእግዚአብሔር ፡ ይሠዋ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ባያመጣው ፥ ያ ፡ ሰው ፡ ከሕዝቡ ፡ ተለይቶ ፡ ይጥፋ ።

፲ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ወይም ፡ በመካከላቸው ፡ ከሚኖሩ ፡ እንግዶች ፡ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ደም ፡ ቢበላ ፥ ደም ፡ በሚበላው ፡ በዚያ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ፊቴን ፡ አከብድበታለሁ ፥ ያንንም ፡ ሰው ፡ ከሕዝቡ ፡ ለይቼ ፡ አጠፋዋለሁ ። ፲፩ የሥጋ ፡ ሕይወት ፡ በደሙ ፡ ውስጥ ፡ ነውና ፤ ደሙም ፡ ከሕይወቱ ፡ የተነሣ ፡ ያስተሰርያልና ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ለነፍሳችሁ ፡ ማስተስረያ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ እኔ ፡ ለእናንተ ፡ ሰጠሁት ። ፲፪ ስለዚህ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡— ከእናንተ ፡ ማንም ፡ ደምን ፡ አይበላም ፥ በመካከላችሁም ፡ ከሚኖሩ ፡ እንግዶች ፡ ማንም ፡ ደምን ፡ አይበላም ፡ አልሁ ።

፲፫ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በመካከላቸውም ፡ ከሚኖሩ ፡ እንግዶች ፡ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ የሚበላ ፡ እንስሳ ፡ ወይም ፡ ወፍ ፡ እያደነ ፡ ቢይዝ ፥ ደሙን ፡ ያፈስሳል ፡ በአፈርም ፡ ይከድነዋል ። ፲፬ የሥጋ ፡ ሁሉ ፡ ሕይወትና ፡ ደሙ ፡ አንድ ፡ ነውና ፡ ስለዚህ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡— የሥጋ ፡ ሁሉ ፡ ሕይወት ፡ ደሙ ፡ ነውና ፡ የሥጋውን ፡ ሁሉ ፡ ደም ፡ አትብሉ ፤ የሚበላውም ፡ ሁሉ ፡ ተለይቶ ፡ ይጥፋ ፡ አልኋቸው ። ፲፭ የሞተውን ፡ ወይም ፡ አውሬ ፡ የሰበረውን ፡ የሚበላ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፥ የአገር ፡ ልጅ ፡ ወይም ፡ እንግዳ ፡ ቢሆን ፥ ልብሱን ፡ ያጥባል ፥ በውኃም ፡ ይታጠባል ፥ እስከ ፡ ማታም ፡ ርኩስ ፡ ይሆናል ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ንጹሕ ፡ ይሆናል ። ፲፮ ልብሱንና ፡ ገላውን ፡ ባያጥብ ፡ ግን ፡ ኃጢአቱን ፡ ይሸከማል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ፪ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝ ። ፫ እንደ ፡ ተቀመጣችሁባት ፡ እንደ ፡ ግብፅ ፡ ምድር ፡ ሥራ ፡ አትሥሩ ፤ እኔም ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ እንደማገባችሁ ፡ እንደ ፡ ከነዓን ፡ ምድር ፡ ሥራ ፡ አትሥሩ ፤ በሥርዓታቸውም ፡ አትሂዱ ። ፬ ፍርዴን ፡ አድርጉ ፥ በእርስዋም ፡ ትሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ሥርዓቴን ፡ ጠብቁ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝ ። ፭ የሚሠራቸው ፡ ሰው ፡ በእነርሱ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራልና ፡ ሥርዓቴንና ፡ ፍርዴን ፡ ጠብቁ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ።

፮ ከእናንተም ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋውን ፡ ይገልጥ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ዘመዱ ፡ ሁሉ ፡ አይቅረብ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ። ፯ የአባትህን ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋና ፡ የእናትህን ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ አትግለጥ ፤ እናትህ ፡ ናት ፤ ኃፍረተ ፡ ሥጋዋን ፡ አትግለጥ ። ፰ የአባትህን ፡ ሚስት ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ አትግለጥ ፤ የአባትህ ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ ነው ። ፱ የእኅትህን ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ አትግለጥ ፤ የአባትህ ፡ ልጅ ፡ ወይም ፡ የእናትህ ፡ ልጅ ፥ በቤት ፡ ወይም ፡ በውጭ ፡ የተወለደች ፡ ብትሆን ፥ ኃፍረተ ፡ ሥጋዋን ፡ አትግለጥ ። ፲ የወንድ ፡ ልጅህን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋዋን ፡ ወይም ፡ የሴት ፡ ልጅህን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ አትግለጥ ፤ የአንተ ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ ነውና ። ፲፩ ከአባትህ ፡ የተወለደችውን ፡ የአባትህን ፡ ሚስት ፡ ልጅ ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ አትግለጥ ፤ እኅትህ ፡ ናት ፤ ኃፍረተ ፡ ሥጋዋን ፡ አትግለጥ ። ፲፪ የአባትህን ፡ እኅት ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ አትግለጥ ፤ የአባትህ ፡ ዘመድ ፡ ናት ። ፲፫ የእናትህን ፡ እኅት ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ አትግለጥ ፤ የእናትህ ፡ ዘመድ ፡ ናት ። ፲፬ የአባትህን ፡ ወንድም ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ አትግለጥ ፥ ወደ ፡ ሚስቱም ፡ አትቅረብ ፤ የአጎትህ ፡ ሚስት ፡ ናት ። ፲፭ የምራትህን ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ አትግለጥ ፤ የልጅህ ፡ ሚስት ፡ ናት ፤ ኃፍረተ ፡ ሥጋዋን ፡ አትግለጥ ። ፲፮ የወንድምህን ፡ ሚስት ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ አትግለጥ ፤ የወንድምህ ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ ነው ። ፲፯ የሴትንና ፡ የሴት ፡ ልጅዋን ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ አትግለጥ ፤ የወንድ ፡ ልጅዋን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ወይም ፡ የሴት ፡ ልጅዋን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋዋን ፡ ትገልጥ ፡ ዘንድ ፡ አታግባ ፤ ዘመዶች ፡ ናቸው ፤ ዝሙት ፡ ነው ። ፲፰ ሚስትህ ፡ በሕይወት ፡ ሳለች ፡ እኅትዋ ፡ ጣውንትዋ ፡ እንዳትሆን ፥ ኃፍረተ ፡ ሥጋዋን ፡ ትገልጥ ፡ ዘንድ ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ እኅትዋን ፡ አታግባ ።

፲፱ እርስዋም ፡ በመርገምዋ ፡ ርኵሰት ፡ ሳለች ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋዋን ፡ ትገልጥ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ሴት ፡ አትቅረብ ። ፳ እንዳትረክስበትም ፡ ከባልንጀራህ ፡ ሚስት ፡ ጋር ፡ አትተኛ ። ፳፩ ከዘርህም ፡ ለሞሎክ ፡ በእሳት ፡ አሳልፈህ ፡ አትስጥ ፥ የአምላክህንም ፡ ስም ፡ አታርክስ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ። ፳፪ ከሴትም ፡ ጋር ፡ እንደምትተኛ ፡ ከወንድ ፡ ጋር ፡ አትተኛ ፤ ጸያፍ ፡ ነገር ፡ ነውና ። ፳፫ እንዳትረክስበትም ፡ ከእንስሳ ፡ ጋር ፡ አትተኛ ፤ ሴት ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ትተኛ ፡ ዘንድ ፡ በእንስሳ ፡ ፊት ፡ አትቁም ፤ የተጠላ ፡ ነገር ፡ ነውና ።

፳፬ በእነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ከፊታችሁ ፡ የማሳድዳቸው ፡ አሕዛብ ፡ ረክሰዋልና ፡ በእነዚህ ፡ ነገሮች ፡ ሁሉ ፡ አትርከሱ ። ፳፭ ምድሪቱም ፡ ረከሰች ፤ ስለዚህ ፡ ኃጢአትዋን ፡ በእርስዋ ፡ ላይ ፡ እመልሳለሁ ፥

ምድሪቱም ፡ የሚኖሩባትን ፡ ሰዎች ፡ ትተፋለች ።
፳፮፤ ሥርዓቴንና ፡ ፍርዴን ፡ ጠብቁ ፤ እናንተም ፡ የአ
ገሩ ፡ ልጆች ፡ በእናንተም ፡ መካከል ፡ የሚኖ
ሩት ፡ እንግዶች ፡ ከዚህ ፡ ርኵሰት ፡ ምንም ፡
፳፯፤ አትሥሩ ፤ ከእናንተ ፡ በፊት ፡ የነበሩ ፡ የአገሩ ፡
ልጆች ፡ ይህን ፡ ርኵሰት ፡ ሁሉ ፡ ሠርተዋልና ፣
፳፰፤ ምድሪቱም ፡ ረክሳለችና ፤ በረከሳችኋት ፡ ጊዜ ፡
ምድሪቱ ፡ ከእናንተ ፡ በፊት ፡ የነበረውን ፡ ሕዝብ ፡
፳፱፤ እንደ ፡ ተፋች ፡ እናንተን ፡ እንዳትተፋችሁ ። ከዚህ ፡
ርኵሰት ፡ ሁሉ ፡ ማናቸውን ፡ የሚያደርግ ፡ ያ ፡
ሰው ፡ ከሕዝቡ ፡ መካከል ፡ ተለይቶ ፡ ይጠፋልና ።
፴፤ ስለዚህ ፡ ከእናንተ ፡ በፊት ፡ የነበሩ ፡ ሰዎች ፡
የሠሩትን ፡ ጸያፍ ፡ የሆነውን ፡ ወግ ፡ ሁሉ ፡ እን
ዳትሠሩ ፣ በእርሱም ፡ እንዳትረክሱ ፡ ሥርዓ
ቴን ፡ ጠብቁ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ
ችሁ ፡ ነኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪፤ ተናገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡
ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ በላቸው ፡— እኔ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ቅዱስ ፡ ነኝና ፡ እናንተ ፡
፫፤ ቅዱሳን ፡ ሁኑ ። ከእናንተ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እና
ቱንና ፡ አባቱን ፡ ይፍራ ፣ ሰንበታቴንም ፡ ጠብቁ ፤
፬፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝ ። ወደ ፡
ጣዖታትም ፡ ዘወር ፡ አትበሉ ፣ ቀልጠው ፡ የተ
ሠሩትንም ፡ የአማልክት ፡ ምስሎች ፡ ለእናንተ ፡
አታድርጉ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡
ነኝ ።
፭፤ የደኅንነትንም ፡ መሥዋዕት ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ ስትሠዉ ፡ እርሱን ፡ ደስ ፡ እንድታሰኙ
፮፤ በት ፡ ሠዉት ። በምትሠዉት ፡ ቀንና ፡ በነጋው ፡
ይበላል ፤ እስከ ፡ ሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡
፯፤ ቢተርፍ ፡ በእሳት ፡ ይቃጠላል ። በሦስተኛ
ውም ፡ ቀን ፡ ቢበላ ፡ ጸያፍ ፡ ነው ፣ ደስም ፡ አያሰ
፰፤ ኝም ፤ የበላውም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ
ውን ፡ ነገር ፡ አርክሶአልና ፡ ኃጢአቱን ፡ ይሸከ
ማል ፤ ያም ፡ ሰው ፡ ከሕዝቡ ፡ ተለይቶ ፡ ይጥፋ ።
፱፤ የምድራችሁንም ፡ መከር ፡ በሰበሰባችሁ ፡
ጊዜ ፡ የእርሻችሁን ፡ ድንበር ፡ ፈጽማችሁ ፡ አት
ጨዱ ፣ የመከሩንም ፡ ቃርሚያ ፡ አትልቀሙ ።
፲፤ የወይንህንም ፡ ቃርሚያ ፡ አትቃርም ፣ የወደቀ
ውንም ፡ የወይንህን ፡ ፍሬ ፡ አትሰብስብ ፤ ለድሆ
ችና ፡ ለእንግዶች ፡ ተወው ፤ እኔ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝ ።
፲፩፤ አትስረቁ ፣ አትካዱም ፣ ከእናንተም ፡ እርስ ፡
፲፪፤ በርሳችሁ ፡ ሐሰት ፡ አትነጋገሩ ። በስሜም ፡ በሐ
ሰት ፡ አትማሉ ፣ የአምላካችሁንም ፡ ስም ፡ አታ
ርክሱ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ።
፲፫፤ በባልንጀራህ ፡ ግፍ ፡ አታድርግ ፣ አትቀማ
ውም ። የሞያተኛው ፡ ዋጋ ፡ እስከ ፡ ነገ ፡ ድረስ ፡
፲፬፤ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ አይደርብህ ። ደንቆሮውን ፡
አትስደብ ፣ በዕውርም ፡ ፊት ፡ ዕንቅፋት ፡ አታ
ድርግ ፣ ነገር ፡ ግን ፡ አምላክህን ፡ ፍራ ፤ እኔ ፡
እግዚአብሔር ፡ ነኝ ።
፲፭፤ በፍርድ ፡ ዓመፃ ፡ አታድርጉ ፤ ለድሀ ፡ አታ
ድላ ፣ ባለ ፡ ጠጋውንም ፡ አታክብር ፤ ነገር ፡ ግን ፡
፲፮፤ ለባልንጀራህ ፡ በእውነት ፡ ፍረድ ። በሕዝብህ ፡
መካከል ፡ በሸንጋይነት ፡ አትዞር ፤ በባልንጀራ
ህም ፡ ደም ፡ ላይ ፡ አትቁም ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡
ነኝ ።
፲፯፤ ወንድምህን ፡ በልብህ ፡ አትጥላው ፤ በባል
ንጀራህ ፡ ምክንያት ፡ ኃጢአት ፡ እንዳይሆን
፲፰፤ ብህ ፤ ገሥጸው ። አትበቀልም ፣ በሕዝብህም ፡
ልጆች ፡ ቂም ፡ አትያዝ ፣ ነገር ፡ ግን ፡ ባልንጀ
ራህን ፡ እንደ ፡ ራስህ ፡ ውደድ ፤ እኔ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ነኝ ።
፲፱፤ ሥርዓቴን ፡ ጠብቁ ። እንስሳህ ፡ ከሌላ ፡ ዓይ
ነት ፡ ጋር ፡ አይደባለቅ ፤ በእርሻህም ፡ ሁለት ፡
ዓይነት ፡ ዘር ፡ አትዝራ ፤ ከሁለት ፡ ዓይነት ፡
ነገር ፡ የተሠራ ፡ ልብስ ፡ አትልበስ ።
፳፤ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ከሴት ፡ ባሪያ ፡ ጋር ፡
ቢተኛ ፣ እርስዋም ፡ ለባል ፡ የተሰጠች ፡ ዋጋዋም ፡
ያልተከፈለ ፡ አርነት ፡ ያልወጣች ፡ ብትሆን ፣
ቅጣት ፡ አለባቸው ፤ አርነት ፡ አልወጣችምና ፡
፳፩፤ አይገደሉም ። እርሱም ፡ የበደሉን ፡ መሥዋዕት ፡
ይዞ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡
ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ይመጣል ፣ ለበደልም ፡ መሥ
፳፪፤ ዋዕት ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ያመጣል ። ካህኑም ፡ ስለ ፡
ሠራው ፡ ኃጢአት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
በበደል ፡ መሥዋዕት ፡ በግ ፡ ያስተሰርይለታል ፤
የሠራውም ፡ ኃጢአት ፡ ይቀርለታል ።
፳፫፤ ወደ ፡ አገሩም ፡ በገባችሁ ፡ ጊዜ ፣ የሚበላ ፡
የፍሬ ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ በተከላችሁም ፡ ጊዜ ፣ ፍሬ
ውን ፡ እንዳልተገረዘ ፡ ትቈጥሩታላችሁ ፤ ሦስት ፡
ዓመት ፡ እንዳልተገረዘ ፡ ይሆንላችኋል ፤ አይበ
፳፬፤ ላም ። የአራተኛውም ፡ ዓመት ፡ ፍሬ ፡ ሁሉ ፡ ለእግ
፳፭፤ ዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ ቅዱስ ፡ ይሁን ። ፍሬውም ፡
ይበዛላችሁ ፡ ዘንድ ፡ የአምስተኛውን ፡ ዓመት ፡
ፍሬ ፡ ብሉ ፤ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝ ።
፳፮፤ ከደሙ ፡ ጋር ፡ ምንም ፡ አትብሉ ፤ አስማ
ትም ፡ አታድርጉ ፣ ሞራ ፡ ገላጭም ፡ አትሁኑ ።
፳፯፤ የራስ ፡ ጠጕራችሁንም ፡ ዙሪያውን ፡ አትከርክ
ሙት ፣ ጢማችሁንም ፡ ዙሪያውን ፡ አትቍረ
፳፰፤ ጡት ። ስለ ፡ ሞተውም ፡ ሥጋችሁን ፡ አትንጩ ፣
ገላችሁንም ፡ አትንቀሱት ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡
ነኝ ።
፳፱፤ ምድሪቱ ፡ ከግልሙትና ፡ ከርኵሰትም ፡ እንዳ
ትሞላ ፡ ሴት ፡ ልጅህን ፡ ታመነዝር ፡ ዘንድ ፡ አታ
፴፤ ርክሳት ። ሰንበታቴን ፡ ጠብቁ ፣ መቅደሴንም ፡
አክብሩ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ።
፴፩፤ ወደ ፡ መናፍስት ፡ ጠሪዎችና ፡ ወደ ፡ ጠንቋ
ዮች ፡ አትሂዱ ፤ እንዳትረክሱባቸውም ፡ አት
ፈልጉአቸው ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ
ችሁ ፡ ነኝ ።
፴፪፤ በሽበታሙ ፡ ፊት ፡ ተነሣ ፣ ሽማግሌውንም ፡
አክብር ፣ አምላክህንም ፡ ፍራ ፤ እኔ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ነኝ ።

፴፫ በአገራችሁ ፡ ውስጥ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እን
፴፬ ግዳ ፡ ቢቀመጥ ፡ ግፍ ፡ አታድርጉበት ። እና
ንተ ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ እንግዶች ፡ ነበራችሁና ፡
ከእናንተ ፡ ጋር ፡ የሚቀመጥ ፡ እንግዳ ፡ እንደ ፡
አገር ፡ ልጅ ፡ ይሁንላችሁ ፥ እርሱንም ፡ እንደ ፡
ራስህ ፡ ውደድ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላ
ካችሁ ፡ ነኝ ።

፴፭ በፍርድ ፥ በመለካትም ፥ በመመዘንም ፥ በመ
፴፮ ስፈርም ፡ ዓመፃ ፡ አታድርጉ ። የእውነትም ፡
ሚዛን ፥ የእውነትም ፡ መመዘኛ ፥ የእውነትም ፡
የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፥ የእውነትም ፡ የኢን ፡ መስ
ፈሪያ ፡ ይሁንላችሁ ፤ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣ
ኋችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ እኔ ፡ ነኝ ።
፴፯ ሥርዓቴን ፡ ሁሉ ፡ ፍርዴንም ፡ ሁሉ ፡ ጠብቁ ፡
አድርጉም ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪ ተናገረው ፦ ደግሞ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡
እንዲህ ፡ በላቸው ፦ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ወይም ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ከሚቀመጡ ፡
እንግዶች ፡ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ዘሩን ፡ ለሞሎክ ፡
ቢሰጥ ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደል ፤ የአገሩ ፡ ሕዝብ ፡
፫ በድንጋይ ፡ ይውገረው ። መቅደሴን ፡ ያረክስ ፡
ዘንድ ፥ የተቀደሰውንም ፡ ስሜን ፡ ያጐስቍል ፡
ዘንድ ፡ ዘሩን ፡ ለሞሎክ ፡ ሰጥቶአልና ፡ እኔ ፡
በዚያ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ፊቴን ፡ አከብዳለሁ ፥ ከሕ
፬ ዝቡም ፡ መካከል ፡ ለይቼ ፡ አጠፋዋለሁ ። ዘሩ
ንም ፡ ለሞሎክ ፡ ሲሰጥ ፥ የአገሩ ፡ ሕዝብ ፡ ያን ፡
፭ ቸል ፡ ቢለው ፡ ባይገድሉትም ፥ እኔ ፡ በዚያ ፡
ሰውና ፡ በቤቱ ፡ ሰቡ ፡ ላይ ፡ ፊቴን ፡ አከብዳለሁ ፤
እርሱንም ፥ ከሞሎክም ፡ ጋር ፡ ያመነዝሩ ፡
ዘንድ ፡ የሚከተሉትን ፡ ሁሉ ፡ ከሕዝባቸው ፡
መካከል ፡ ለይቼ ፡ አጠፋለሁ ።

፮ መናፍስት ፡ ጠሪዎችንና ፡ ጠንቋዮችንም ፡
በሚከተል ፥ በሥራቸውም ፡ በሚያመነዝር ፥
በዚያ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ፊቴን ፡ አከብዳለሁ ፥ ከሕ
፯ ዝቡም ፡ መካከል ፡ ለይቼ ፡ አጠፋዋለሁ ። እን
ግዲህ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝና ፡
ሰውነታችሁን ፡ ቀድሱ ፥ ቅዱሳንም ፡ ሁኑ ።
፰ ሥርዓቴን ፡ ጠብቁ ፥ አድርጉትም ፤ እኔ ፡ የም
፱ ቀድሳችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ። ማናቸውም ፡
ሰው ፡ አባቱን ፡ ወይም ፡ እናቱን ፡ ቢሰድብ ፡
ፈጽሞ ፡ ይገደል ፥ አባቱንና ፡ እናቱን ፡ ሰድቦ
አልና ፤ ደሙ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ነው ።

፲ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ከሌላ ፡ ሰው ፡ ሚስት ፡
ወይም ፡ ከባልንጀራው ፡ ሚስት ፡ ጋር ፡ ቢያመ
ነዝር ፡ አመንዝራውና ፡ አመንዝራይቱ ፡ ፈጽ
፲፩ መው ፡ ይገደሉ ። ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ከአባቱ ፡
ሚስት ፡ ጋር ፡ ቢተኛ ፡ የአባቱን ፡ ኃፍረተ ፡
ሥጋ ፡ ገልጦአል ፤ ሁለቱ ፡ ፈጽመው ፡ ይገደሉ ፤
፲፪ ደማቸው ፡ በላያቸው ፡ ነው ። ማናቸውም ፡
ሰው ፡ ከምራቱ ፡ ጋር ፡ ቢተኛ ፡ ሁለቱ ፡ ፈጽ
መው ፡ ይገደሉ ፤ ጸያፍ ፡ ነገር ፡ አድርገዋል ፤
ደማቸው ፡ በላያቸው ፡ ነው ። ማናቸውም ፡ ፲፫
ሰው ፡ ከሴት ፡ ጋር ፡ እንደሚተኛ ፡ ከወንድ ፡
ጋር ፡ ቢተኛ ፡ ሁለቱ ፡ ጸያፍ ፡ ነገር ፡ አድርገ
ዋል ፤ ፈጽመው ፡ ይገደሉ ፤ ደማቸው ፡ በላያ
ቸው ፡ ነው ። ማናቸውም ፡ ሰው ፡ እናቲቱንና ፡ ፲፬
ልጂቱን ፡ ቢያገባ ፡ ርኵሰት ፡ ነው ፤ በመካከላ
ችሁ ፡ ኃጢአት ፡ እንዳይሆን ፡ እርሱና ፡ እነርሱ ፡
በእሳት ፡ ይቃጠሉ ። ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ከእ ፲፭
ንስሳ ፡ ጋር ፡ ቢገናኝ ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደል ፤ እንስ
ሳይቱንም ፡ ግደሉአት ። ማናቸይቱም ፡ ሴት ፡ ፲፮
ወደ ፡ እንስሳ ፡ ብትቀርብ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡
ብትገናኝ ፥ ሴቲቱንና ፡ እንስሳውን ፡ ግደል ፤
ፈጽመው ፡ ይገደሉ ፤ ደማቸው ፡ በላያቸው ፡
ነው ።

ማናቸውም ፡ ሰው ፡ የአባቱን ፡ ልጅ ፡ ወይም ፡ ፲፯
የእናቱን ፡ ልጅ ፡ እኅቱን ፡ ቢያገባ ፥ ኃፍረተ ፡
ሥጋዋንም ፡ ቢያይ ፥ እርስዋም ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ
ውን ፡ ብታይ ፥ ይህ ፡ ጸያፍ ፡ ነገር ፡ ነው ፤ በሕ
ዝባቸውም ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ይገደሉ ፤ የእኅ
ቱን ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ ገልጦአልና ፡ ኃጢአቱን ፡
ይሸከማል ። ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ከበለ ፡ መር ፲፰
ገም ፡ ሴት ፡ ጋር ፡ ቢተኛ ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋዋንም ፡
ቢገልጥ ፥ ፈሳሽዋን ፡ ገልጦአልና ፥ እርስዋም ፡
የደምዋን ፡ ፈሳሽ ፡ ገልጣለችና ፡ ሁለቱ ፡ ከሕዝ
ባቸው ፡ መካከል ፡ ተለይተው ፡ ይጥፉ ። የአባ ፲፱
ትህን ፡ ወይም ፡ የእናትህን ፡ እኅት ፡ ኃፍረተ ፡
ሥጋ ፡ አትግለጥ ፤ ይህን ፡ የሚያደርግ ፡ የዘመ
ድን ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ ገልጦአል ፤ ኃጢአታ
ቸውን ፡ ይሸከማሉ ። ሰውም ፡ ከአጎቱ ፡ ሚስት ፡ ፳
ጋር ፡ ቢተኛ ፥ የአጎቱን ፡ ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡
ገልጦአል ፤ ኃጢአታቸውን ፡ ይሸከማሉ ፤ ያለ ፡
ልጅ ፡ ይሞታሉ ። ሰውም ፡ የወንድሙን ፡ ፳፩
ሚስት ፡ ቢያገባ ፡ ርኵሰት ፡ ነው ፤ የወንድሙን ፡
ኃፍረተ ፡ ሥጋ ፡ ገልጦአል ፤ ያለ ፡ ልጅ ፡ ይሆ
ናሉ ።

እንግዲህ ፡ ትቀመጡበት ፡ ዘንድ ፡ የማገባችሁ ፡ ፳፪
ምድር ፡ እንዳትተፋችሁ ፡ ሥርዓቴን ፡ ሁሉ ፥
ፍርዴንም ፡ ሁሉ ፡ ጠብቁ ፥ አድርጉትም ።
ከፊታችሁ ፡ በምጥላቸውም ፡ ሕዝብ ፡ ወግ ፡ አት ፳፫
ሂዱ ፤ ይህን ፡ ሁሉ ፡ አድርገዋልና ፡ ተጸየፍኋ
ቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ እናንተን ፦ ምድራቸ ፳፬
ውን ፡ ትወርሳላችሁ ፤ ትወርሱአትም ፡ ዘንድ ፡
ወተትና ፡ ማር ፡ የምታፈስሰውን ፡ ምድር ፡ እሰ
ጣችኋለሁ ፡ አልኋችሁ ። እኔ ፡ ከአሕዛብ ፡ የለ
የኋችሁ ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ።
እንግዲህ ፡ ንጹሑን ፡ እንስሳ ፡ ከርኩሱ ፥ ንጹ ፳፭
ሑንም ፡ ወፍ ፡ ከርኩሱ ፡ ትለያላችሁ ፤ ርኩ
ሶች ፡ ናቸው ፡ ብዬ ፡ በለየኋቸው ፡ በእንስሳና ፡
በወፍ ፡ በምድርም ፡ ተንቀሳቃሽ ፡ ሁሉ ፡ ነፍሳ
ችሁን ፡ አታርክሱ ። እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፳፮
ቅዱስ ፡ ነኝና ፥ ለእኔም ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ከአሕ
ዛብ ፡ ለይቻችኋለሁና ፡ ቅዱሳን ፡ ትሆኑልኛላ
ችሁ ።

ሰው ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ መናፍስትን ፡ ቢጠሩ ፡ ፳፯

ወይም ፡ ጠንቋዮች ፡ ቢሆኑ ፡ ፈጽመው ፡ ይገ
ደሉ ፤ በድንጋይ ፡ ይውገሩአቸው ፤ ደማቸው ፡
በላያቸው ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— ለካህናቱ ፡ ለአ
ሮን ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፡
አለው ፡— ማንም ፡ ሰው ፡ ከሕዝቡ ፡ ስለ ፡ ሞተው ÷
፪፤ ከሚቀርበው ፡ ዘመዱ ÷ ከእናቱ ÷ ወይም ፡ ከአ
ባቱ ÷ ወይም ፡ ከወንድ ፡ ልጁ ÷ ወይም ፡ ከሴት ፡
ልጁ ÷ ወይም ፡ ከወንድሙ ፡ በቀር ፡ አይርከስ ።
፫፤ ወይም ፡ የቀረበችው ፡ ያልተጋባች ፡ ድንግል ፡
፬፤ እኅቱ ፡ በእርስዋ ፡ ይርከስ ። የሕዝቡ ፡ አለቃ ፡
፭፤ ራሱን ፡ ያጐሰቍል ፡ ዘንድ ፡ አይርከስ ። ራሳቸ
ውን ፡ አይላጩ ÷ ጢማቸውንም ፡ አይላጩ ÷ ሥጋ
፮፤ ቸውንም ፡ አይንጩ ። ለአምላካቸው ፡ ቅዱሳን ፡
ይሁኑ ÷ የአምላካቸውንም ፡ ስም ፡ አያጐስቍሉ ፤
የእግዚአብሔርን ፡ የእሳት ፡ ቍርባንና ፡ የአም
ላካቸውን ፡ እንጀራ ፡ ያቀርባሉና ፡ ቅዱሳን ፡
፯፤ ይሁኑ ። ለአምላኩ ፡ የተቀደሰ ፡ ነውና ፡ ጋለሞ
ታን ፡ ሴት ፡ ወይም ፡ የረከሰችውን ፡ አያግባ ፤
ወይም ፡ ከባልዋ ፡ የተፈታችውን ፡ አያግባ ።
፰፤ የአምላክህን ፡ እንጀራ ፡ ያቀርባልና ፡ ስለዚህ ፡
ትቀድሰዋለህ ፤ እኔም ፡ የምቀድሳችሁ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ቅዱስ ፡ ነኝና ፡ እርሱ ፡ ቅዱስ ፡ ይሁ
፱፤ ንልህ ። የካህንም ፡ ልጅ ፡ ራስዋን ፡ በግልሙ
ትና ፡ ብታረክስ ፡ አባትዋን ፡ ታረክሰዋለች ፤ በእ
ሳት ፡ ትቃጠል ።
፲፤ በራሱም ፡ ላይ ፡ የቅባት ፡ ዘይት ፡ የፈሰሰበት ÷
የክህነትም ፡ ልብስ ፡ ይለብስ ፡ ዘንድ ፡ የተቀደሰ ፡
ከወንድሞቹ ፡ የበለጠው ፡ ካህን ፡ ራሱን ፡ አይ
፲፩፤ ግለጥ ፡ ልብሱንም ፡ አይቅደድ ። ወደ ፡ በድ
ንም ፡ ሁሉ ፡ አይግባ ÷ በአባቱም ፡ ወይም ፡ በእ
፲፪፤ ናቱ ፡ አይርከስ ። የአምላኩም ፡ ቅባት ፡ ዘይት ፡
ቅዱስነት ፡ በላዩ ፡ ነውና ፡ ከመቅደስ ፡ አይውጣ ÷
የአምላኩንም ፡ መቅደስ ፡ አያርክስ ፤ እኔ ፡ እግ
፲፫፤ ዚአብሔር ፡ ነኝ ። እርሱም ፡ ሚስትን ፡ በድንግ
፲፬፤ ልናዋ ፡ ያግባ ። ባልዋ ፡ የሞተባትን ÷ ወይም ፡
የተፋታችውን ÷ ወይም ፡ ጋለሞታይቱን ፡ አያ
ግባ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከሕዝቡ ፡ ድንግሊቱን ፡ ያግባ ።
፲፭፤ እኔም ፡ የምቀድሰው ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝና ፡
በሕዝቡ ፡ መካከል ፡ ዘሩን ፡ አያጐስቍል ።
፲፮፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፲፯፤ ተናገረው ፡— ለአሮን ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገ
ረው ፡— ከዘርህ ፡ በትውልዳቸው ፡ ነውር ፡ ያለ
በት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የአምላኩን ፡ እንጀራ ፡ ያቀ
፲፰፤ ርብ ፡ ዘንድ ፡ አይቅረብ ። ዕውር ÷ ወይም ፡ አን
ካሳ ÷ ወይም ፡ አፍንጫ ፡ ደፍጣጣ ÷ ወይም ፡
፲፱፤ ትርፍ ፡ አካል ፡ ያለው ÷ ወይም ፡ እግረ ፡ ሰባራ ÷
፳፤ ወይም ፡ እጀ ፡ ሰባራ ÷ ወይም ፡ ጐባጣ ÷ ወይም ፡
ድንክ ÷ ወይም ፡ ዓይነ ፡ መጭማጫ ÷ ወይም ፡
እከካም ÷ ወይም ፡ ቋቍቻም ÷ ወይም ፡ ጃንደ
፳፩፤ ረባ ÷ ነውረኛ ፡ ሁሉ ፡ አይቅረብ ። ከካህኑ ፡ ከአ
ሮን ፡ ዘር ፡ ነውር ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ የእግዚአብ
ሔርን ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ያቀርብ ፡ ዘንድ ፡ አይ
ቅረብ ፤ ነውረኛ ፡ ነው ፤ የአምላኩን ፡ እንጀራ ፡
ያቀርብ ፡ ዘንድ ፡ አይቅረብ ። የቅዱሱንና ፡ የቅ ፳፪፤
ዱሰ ፡ ቅዱሳኑን ፡ የአምላኩን ፡ እንጀራ ፡ ይብላ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ነውረኛ ፡ ነውና ፡ መቅደሶቼን ፡ እን ፳፫፤
ዳያረክስ ፡ ወደ ፡ መጋረጃው ፡ አይግባ ÷ ወደ ፡
መሠዊያውም ፡ አይቅረብ ፤ የምቀድሳቸው ፡
እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ። ሙሴም ፡ ይህን ፡ ፳፬፤
ለአሮን ÷ ለልጆቹም ÷ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
ሁሉ ፡ ነገረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፩፤
ተናገረው ፡— የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ለእኔ ፡ ከሚ ፪፤
ቀድሱአቸው ፡ ከቅዱሳን ፡ ነገሮች ፡ ራሳቸውን ፡
እንዲለዩ ÷ የተቀደሰውንም ፡ ስሜን ፡ እንዳያረ
ክሱ ፡ ለአሮንና ፡ ለልጆቹ ፡ ንገራቸው ፤ እኔ ፡
እግዚአብሔር ፡ ነኝ ። እንዲህ ፡ በላቸው ፡— ፫፤
ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ከዘራችሁ ፡ በትውልዳችሁ ፡
ርኵሰት ፡ እያለበት ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ ወደሚቀድሱት ፡ ወደ ፡ ቅዱስ ፡
ነገር ፡ ቢቀርብ ÷ ያ ፡ ሰው ፡ ከፊቴ ፡ ተለይቶ ፡
ይጥፋ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ። ከአሮን ፡ ፬፤
ዘር ፡ ለምጽ ፡ ወይም ፡ ፈሳሽ ፡ ነገር ፡ ያለበት ፡
ሁሉ ፡ ንጹሕ ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡ ከተቀደሰው ፡
አይብላ ። ከበድንም ፡ የተነሣ ፡ ርኩስ ፡ የሆነውን ÷
ወይም ፡ ዘሩ ፡ ከእርሱ ፡ የሚፈስስበትን ፡ የሚ
ነካ ÷ ወይም ፡ የሚያረክሰውን ፡ ተንቀሳቃሽ ÷ ፭፤
ወይም ፡ በሁሉ ፡ ዓይነት ፡ የረከሰውን ፡ ሰው ፡
የሚነካ ÷ እነዚህን ፡ ሁሉ ፡ የሚነካ ፡ ሰው ፡ እስከ ፡ ፮፤
ማታ ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡ ይሆናል ፤ ገላውን ፡ በውኃ ፡
ካልታጠበ ፡ ከተቀደሰው ፡ አይብላ ። ፀሐይም ፡ ፯፤
በገባች ፡ ጊዜ ፡ ንጹሕ ፡ ይሆናል ፤ ከዚያም ፡
በኋላ ፡ እንጀራው ፡ ነውና ፡ ከተቀደሰው ፡ ይብላ ።
በእርሱም ፡ እንዳይረክስ ÷ የሞተውን ፡ አው ፰፤
ሬም ፡ የሰበረውን ፡ አይብላ ፤ እኔ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ነኝ ። ቢያረክሱአት ፡ እንዳይሞቱ ፡ ስለ ፡ ፱፤
እርስዋም ፡ ኃጢአትን ፡ እንዳይሸከሙ ÷ ሕግን ፡
ይጠብቁ ፤ የምቀድሳቸው ፡ እኔ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ነኝ ።
ልዩ ፡ ሰው ፡ ከተቀደሰው ፡ አይብላ ፡ የካህኑም ፡ ፲፤
እንግዳ ፡ ደመወዘኛውም ፡ ከተቀደሰው ፡ አይ
ብላ ። ካህኑ ፡ ግን ፡ በገንዘቡ ፡ ባሪያ ፡ ቢገዛ ፡ ፲፩፤
እርሱ ፡ ይብላው ፤ በቤቱም ፡ የተወለዱት ፡ ከእ
ንጀራው ፡ ይብሉ ። የካህንም ፡ ልጅ ፡ ከልዩ ፡ ፲፪፤
ሰው ፡ ጋር ፡ ብትጋባ ÷ እርስዋ ፡ ከተቀደሰው ፡
ቍርባን ፡ አትብላ ። የካህን ፡ ልጅ ፡ ግን ፡ ባልዋ ፡ ፲፫፤
ቢሞት ÷ ወይም ፡ ብትፋታ ÷ ልጅም ፡ ባይኖ
ራት ÷ በብላቴንነትዋ ፡ እንደ ፡ ነበረች ፡ ወደ ፡
አባትዋ ፡ ቤት ፡ ብትመለስ ÷ ከአባትዋ ፡ እንጀራ ፡
ትብላ ፤ ልዩ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ አይብላ ።
ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ሳያውቅ ፡ ከተቀደሰው ፡ ፲፬፤
ቢበላ ፡ አምስተኛ ፡ እጅ ፡ ጨምሮ ፡ የተቀደሰ
ውን ፡ ለካህኑ ፡ ይስጥ ። የምቀድሳቸውም ፡ እግ ፲፭፤፲፮፤

ዚአብሔር ፡ እኔ ፡ ነኝና ፡ ከተቀደሰው ፡ በበሉ ፡
ጊዜ ፡ ኃጢአትንና ፡ በደልን ፡ እንዳይሸከሙ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚያቀርቡትን ፡ በእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ የተቀደሰውን ፡ ነገር ፡
አያርክሱ ።

፲፯ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፲፰ ፡ ተናገረው ፡— ለአሮንና ፡ ለልጆቹ ፡ ለእስራኤ
ልም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራ
ቸው ፡— ከእስራኤል ፡ ቤት ፡ ወይም ፡ ከእናንተ ፡
መካከል ፡ ከሚቀመጡት ፡ እንግዶች ፡ ማናቸ
ውም ፡ ሰው ፡ ስእለቱን ፡ ሁሉ ፥ በፈቃዱም ፡
የሚያቀርበውን ፡ ሁሉ ፥ ለእግዚአብሔር ፡ ለሚ
ቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የሚያቀርበውን ፡ ቍር
፲፱ ፡ ባን ፡ ቢያቀርብ ፥ ይሠምርላችሁ ፡ ዘንድ ፡ ከበሬ ፡
ወይም ፡ ከበግ ፡ ወይም ፡ ከፍየል ፡ ነውር ፡ የሌ
፳ ፡ ለበትን ፡ ተባቱን ፡ አቅርቡ ። ነገር ፡ ግን ፡ አይ
ሠምርላችሁምና ፡ ነውር ፡ ያለበትን ፡ አታቅ
፳፩ ፡ ርቡ ። ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ስእለቱን ፡ ለመፈ
ጸም ፡ ወይም ፡ በፈቃዱ ፡ ለማቅረብ ፡ የደኅንነ
ትን ፡ መሥዋዕት ፥ ወይም ፡ በሬን ፡ ወይም ፡
በግን ፥ ለእግዚአብሔር ፡ ቢያቀርብ ፥ ይሠምር
ለት ፡ ዘንድ ፡ ፍጹም ፡ ይሁን ፥ ነውርም ፡ አይ
፳፪ ፡ ሁንበት ። ዕውር ፡ ወይም ፡ ሰባራ ፡ ወይም ፡
ጕንድሽ ፡ ወይም ፡ የሚመግል ፡ ቍስል ፡ ያለ
በት ፡ ወይም ፡ እከካም ፡ ወይም ፡ ቋቍቻም ፡
ቢሆን ፥ እነዚህን ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አታ
ቅርቡ ፤ እነዚህንም ፡ ለእሳት ፡ ቍርባን ፡ በመ
ሠዊያው ፡ ላይ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አታሳርጉ ።
፳፫ ፡ በሬው ፡ ወይም ፡ በጉ ፡ የተጨመረበት ፡ ወይም ፡
የጐደለበት ፡ ነገር ፡ ቢሆን ፥ ለፈቃድ ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ማቅረብ ፡ ትችላለህ ፤ ለስእለት ፡ ግን ፡ አይ
፳፬ ፡ ሠምርም ። የተሰነጋውን ፡ ወይም ፡ የተቀጠ
ቀጠውን ፡ ወይም ፡ የተሰበረውን ፡ ወይም ፡ የተ
ቈረጠውን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አታቅርቡ ፤ በም
፳፭ ፡ ድራችሁም ፡ እነዚህን ፡ አትሠዉ ። ከእነዚህም ፡
ከእንግዳ ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ ለአምላካችሁ ፡ እንጀራ ፡
አታቅርቡ ፤ ርኵሰትም ፡ ነውርም ፡ አለባቸውና ፡
አይሠምሩላችሁም ።

፳፮ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፳፯ ፡ ተናገረው ፡— በሬ ፡ ወይም ፡ በግ ፡ ወይም ፡ ፍየል ፡
ሲወለድ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ከእናቱ ፡ ጋር ፡ ይቀመጥ ፤
በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ የሠመረ ፡ ይሆ
፳፰ ፡ ናል ። ላም ፡ ወይም ፡ በግ ፡ ብትሆን ፡ እርስዋ
፳፱ ፡ ንና ፡ ልጅዋን ፡ በአንድ ፡ ቀን ፡ አትረዱ ። የም
ስጋናንም ፡ መሥዋዕት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስት
፴ ፡ ሠዉ ፡ እንዲሠምርላችሁ ፡ ሠዉለት ። በዚያው ፡
ቀን ፡ ይበላል ፤ ከእርሱ ፡ እስከ ፡ ነገ ፡ ምንም ፡
፴፩ ፡ አትተዉ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ። ትእዛዛ
ቴን ፡ ጠብቁ ፥ አድርጉትም ፤ እኔ ፡ እግዚአብ
፴፪ ፡ ሔር ፡ ነኝ ። የተቀደሰውንም ፡ ስሜን ፡ አታር
ክሱ ፤ እኔ ፡ ግን ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካ
፴፫ ፡ ከል ፡ እቀደሳለሁ ፤ የምቀድሳችሁ ፥ አምላካች
ሁም ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣ
ኋችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ። እኔ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ነኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪ ፡ ተናገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡
ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ብላ
ችሁ ፡ የምታውጁአቸው ፡ በዓላቶቼ ፥ የእግ
፫ ፡ ዚአብሔር ፡ በዓላት ፥ እነዚህ ፡ ናቸው ። ስድ
ስት ፡ ቀን ፡ ሥራ ፡ ይሠራል ፤ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡
ግን ፡ የዕረፍት ፡ ሰንበት ፡ ነው ፤ የተቀደሰ ፡
ጉባኤ ፡ ይሆንበታል ፤ ምንም ፡ ሥራ ፡ አትሠ
ሩም ፤ በምትኖሩበት ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ሰንበት ፡ ነው ።

፬ ፡ እነዚህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ በዓላት ፥ በየዘመና
ቸው ፡ የምታውጁአቸው ፥ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡
፭ ፡ ናቸው ። በመጀመሪያው ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ አራ
ተኛው ፡ ቀን ፡ ሲመሽ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፋሲካ ፡
፮ ፡ ነው ። በዚህም ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ አምስተኛው ፡
ቀን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የቂጣ ፡ በዓል ፡ ነው ፤
፯ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ቂጣ ፡ እንጀራ ፡ ብሉ ። በመጀመ
ሪያው ፡ ቀን ፡ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ይሁንላችሁ ፤
፰ ፡ የተግባር ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አትሥሩበት ። ሰባት ፡
ቀንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡
አቅርቡ ፤ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡
ነው ፤ የተግባር ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አትሥሩበት ።

፱ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፲ ፡ ተናገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡
ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— ወደምሰጣችሁ ፡ ምድር ፡
በገባችሁ ፡ ጊዜ ፥ መከሩንም ፡ ባጨዳችሁ ፡ ጊዜ ፥
የእናንተን ፡ መከር ፡ በኵራት ፡ ነዶ ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡
፲፩ ፡ አምጡ ፤ እርሱም ፡ ነዶውን ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ እንዲሠምርላችሁ ፡ ይወዝውዘው ፤ በማ
ግስቱ ፡ ከሰንበት ፡ በኋላ ፡ ካህኑ ፡ ይወዝውዘው ።
፲፪ ፡ ነዶውንም ፡ በወዘወዛችሁበት ፡ ቀን ፡ ነውር ፡ የሌ
ለበትን ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፡ ለሚ
ቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አቅ
፲፫ ፡ ርቡ ። የእህልም ፡ ቍርባን ፡ ከመስፈሪያው ፡
ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሁለት ፡ እጅ ፡ የሆነ ፡ በዘይት ፡
የተለወሰ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ ለእሳት ፡ ቍርባን ፡
ይሁን ፤ የመጠጡም ፡ ቍርባን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡
የኢን ፡ መስፈሪያ ፡ አራተኛ ፡ እጅ ፡ ይሁን ።
፲፬ ፡ እንጀራውንም ፥ የተጠበሰውንም ፡ እሸት ፥ ለም
ለሙንም ፡ እሸት ፡ የአምላካችሁን ፡ ቍርባን ፡
እስከምታቀርቡበት ፡ እስከዚህ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡
አትብሉ ። ይህ ፡ በምትቀመጡበት ፡ አገር ፡
ሁሉ ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡
ነው ።

፲፭ ፡ የወዘወዛችሁትን ፡ ነዶ ፡ ከምታመጡበት ፡
ቀን ፡ በኋላ ፡ ከሰንበት ፡ ማግስት ፡ ፍጹም ፡ ሰባት ፡
፲፮ ፡ ጊዜ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ቍጠሩ ፤ እስከ ፡ ሰባተኛ ፡
ሰንበት ፡ ማግስት ፡ ድረስ ፡ አምሳ ፡ ቀን ፡ ቍጠሩ ፤
አዲሱንም ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ወደ ፡ እግዚአ

፲፯፤ ብሔር ፡ አቅርቡ ። ከየማደሪያችሁ ፡ ከመስፈሪ
ያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሁለት ፡ እጅ ፡ ከሆነ ፡ መል
ካም ፡ ዱቄት ፡ የተሠራ ፡ ሁለት ፡ የመወዝወዝ ፡
እንጀራ ፡ ታመጣላችሁ ፤ ለእግዚአብሔር ፡
ለበኵራት ፡ ቍርባን ፡ እንዲሆን ፡ በእርሾ ፡ ይጋ
፲፰፤ ገራል ። ከእንጀራውም ፡ ጋር ፡ ነውር ፡ የሌለባ
ቸውን ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ሰባት ፡ ጠቦቶች ፣
አንድ ፡ ወይፈንም ፣ ሁለትም ፡ አውራ ፡ በጎች ፡
ታቀርባላችሁ ፤ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃጠል ፡
መሥዋዕት ፡ ይሁኑ ፤ ከእህልም ፡ ቍርባን ፣
ከመጠጡም ፡ ቍርባን ፡ ጋር ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡
፲፱፤ ይሁኑ ። አንድም ፡ አውራ ፡ ፍየል ፡ ለኃጢአት ፡
መሥዋዕት ፣ ሁለትም ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡
ጠቦቶች ፡ ለደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ አቅርቡ ።
፳፤ ካህኑም ፡ ከበኵራቱ ፡ እንጀራ ፡ ከሁለቱም ፡ ጠቦ
ቶች ፡ ጋር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለመወዝ
ወዝ ፡ ቍርባን ፡ ይወዘውዛቸዋል ፤ ለእግዚአብ
ሔር ፡ የተቀደሰ ፡ ፈንታ ፡ ነው ፤ ለካህኑ ፡ ይሁን ።
፳፩፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ይሆንላችሁ ፡
ዘንድ ፡ ታውጃላችሁ ፤ የተግባር ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡
አታድርጉበት ፤ በምትቀመጡበት ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡
ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ነው ።
፳፪፤ የምድራችሁንም ፡ መከር ፡ በሰበሰባችሁ ፡
ጊዜ ፡ የእርሻችሁን ፡ ድንበር ፡ ፈጽማችሁ ፡
አትጨዱ ፣ የመከሩንም ፡ ቃርሚያ ፡ አትልቀሙ ፤
ለድሆችና ፡ ለእንግዶች ፡ ተዉት ፤ እኔ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝ ።
፳፫፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፳፬፤ ተናገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡
ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— በሰባተኛው ፡ ወር ፡ በመ
ጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ዕረፍት ፣ በመለከት ፡ ድምፅ ፡
መታሰቢያ ፣ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ይሁንላችሁ ።
፳፭፤ የተግባር ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አታድርጉበት ፣ ለእ
ግዚአብሔርም ፡ የእሳት ፡ ቍርባንን ፡ አቅርቡ ።
፳፮፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፳፯፤ ተናገረው ፡— በዚህ ፡ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ አሥ
ረኛው ፡ ቀን ፡ የማስተስረያ ፡ ቀን ፡ ነው ፤ የተ
ቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ይሁንላችሁ ፤ ሰውነታችሁን ፡
አስጨንቋት ፣ ለእግዚአብሔርም ፡ የእሳት ፡
፳፰፤ ቍርባንን ፡ አቅርቡ ። በአምላካችሁም ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ማስተስረያ ፡ ይሆንላችሁ ፡
ዘንድ ፡ የማስተስረያ ፡ ቀን ፡ ነውና ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡
፳፱፤ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አትሥሩ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ የማ
ይዋረድ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከሕዝቡ ፡ ተለይቶ ፡
፴፤ ይጥፋ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ሥራ ፡ የሚሠራውን ፡
ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከሕዝቡ ፡ መካከል ፡ አጠፋዋለሁ ።
፴፩፤ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አታድርጉበት ፤ በምትቀመጡ
በት ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ የዘላለም ፡
፴፪፤ ሥርዓት ፡ ነው ። የዕረፍት ፡ ሰንበት ፡ ይሁንላ
ችሁ ፣ ሰውነታችሁንም ፡ አዋርዱ ፤ በወሩ ፡
በዘጠኘኛው ፡ ቀን ፡ በማታ ፡ ጊዜ ፣ ከማታ ፡
ጀምራችሁ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፣ ሰንበታች
ሁን ፡ አድርጉ ።

፴፫፤ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተና
፴፬፤ ገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡
ንገራቸው ፡— በዚህ ፡ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ ከአ
ሥራ ፡ አምስተኛው ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ ሰባት ፡
ቀን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የዳስ ፡ በዓል ፡ ይሆናል ።
፴፭፤ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ይሁን ፤
፴፮፤ የተግባር ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አታድርጉበት ። ሰባት ፡
ቀን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የእሳት ፡ ቍርባንን ፡ አቅ
ርቡ ፤ በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡
ይሁንላችሁ ፣ ለእግዚአብሔርም ፡ የሚቃጠለ
ውን ፡ ቍርባን ፡ አቅርቡ ፤ ዋና ፡ ጉባኤ ፡ ነው ፤
የተግባር ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አታድርጉበት ።
፴፯፤ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፣ የእህሉንም ፡
ቍርባን ፣ መሥዋዕቱንም ፣ የመጠጡንም ፡
ቍርባን ፣ በየቀኑ ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ታቀርቡባቸው ፡ ዘንድ ፡ የተቀ
ደሱ ፡ ጉባኤዎች ፡ እንዲሆኑ ፡ የምታውጁአቸው ፡
የእግዚአብሔር ፡ በዓላት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።
፴፰፤ እነዚህም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ሰንበታት ፡ ሌላ ፣
ለእግዚአብሔርም ፡ ከምትሰጡት ፡ ከስጦታችሁ ፡
ሌላ ፣ ከስእለታችሁም ፡ ሁሉ ፡ ሌላ ፣ በፈቃዳ
ችሁም ፡ ከምታቀርቡአቸው ፡ ሁሉ ፡ ሌላ ፡
ናቸው ።
፴፱፤ ከሰባተኛውም ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ አምስተ
ኛው ፡ ቀን ፡ የምድሩን ፡ ፍሬ ፡ ከከማቻችሁ ፡
በኋላ ፣ የእግዚአብሔርን ፡ በዓል ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡
ጠብቁ ፤ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ዕረፍት ፡ ይሁን ፣
፵፤ በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ ዕረፍት ፡ ይሁን ። በመ
ጀመሪያው ፡ ቀን ፡ የመልካም ፡ ዛፍ ፡ ፍሬ ፣ የሰ
ሌን ፡ ቅርንጫፍ ፣ የለመለመውን ፡ ዛፍ ፡ ቅርን
ጫፍ ፣ የወንዝም ፡ አኻያ ፡ ዛፍ ፡ ውሰዱ ፤ በአ
ምላካችሁም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሰባት ፡
፵፩፤ ቀን ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ። ይህንንም ፡ በዓል ፡ በየዓ
መቱ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አድርጉ ፤
ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ነው ፤
፵፪፡፵፫፤ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ ትጠብቁታላችሁ ። ሰባት ፡
ቀን ፡ በዳሶች ፡ ውስጥ ፡ ትቀመጣላችሁ ፤ ከግ
ብፅ ፡ ምድር ፡ በወጣኋቸው ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤ
ልን ፡ ልጆች ፡ በዳስ ፡ ውስጥ ፡ እንዳስቀመጥኋ
ቸው ፡ የልጅ ፡ ልጆቻችሁ ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፣
በእስራኤል ፡ ያሉት ፡ የአገር ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡
በዳስ ፡ ውስጥ ፡ ይቀመጡ ፤ እኔ ፡ እግዚአብ
፵፬፤ ሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝ ። ሙሴም ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ በዓላት ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተና
ገረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪፤ ተናገረው ፡— መብራቱን ፡ ሁልጊዜ ፡ እንድታበ
ራበት ፡ ለመብራት ፡ ጥሩ ፡ ተወቅጦ ፡ የተጠለለ ፡
የወይራ ፡ ዘይት ፡ ያመጡልህ ፡ ዘንድ ፡ የእስራ
ኤልን ፡ ልጆች ፡ እዘዛቸው ። በምስክሩ ፡ መጋ
፫፤ ረጃ ፡ ውጭ ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡
አሮን ፡ ከማታ ፡ እስከ ፡ ማለዳ ፡ ድረስ ፡ በእግዚ

አብሔር ፡ ፊት ፡ ሁልጊዜ ፡ ያሰናዳው ፤ ለዘላ
ለም ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ ሥርዓት ፡ ይሁን ።
፬ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በጥሩ ፡ መቅረዝ ፡ ላይ ፡
መብራቶቹን ፡ ሁልጊዜ ፡ ያሰናዳቸው ።
፭ መልካሙንም ፡ ዱቄት ፡ ወስደህ ፡ አሥራ ፡
ሁለት ፡ ኅብስት ፡ ጋግር ፤ በአንድ ፡ ኅብስት ፡
ውስጥ ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሁለት ፡
፮ እጅ ፡ ይሁን ። እነዚህንም ፡ ስድስት ፡ ስድስቱን ፡
በሁለት ፡ ተርታ ፡ አድርገህ ፡ በእግዚአብሔር ፡
፯ ፊት ፡ በጥሩ ፡ ገበታ ፡ ላይ ፡ አኑራቸው ። ለእግዚአ
ብሔርም ፡ ለእሳት ፡ ቍርባን ፡ በእንጀራው ፡ ላይ ፡
ለመታሰቢያ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ በሁለቱ ፡ ተርታ ፡
፰ ላይ ፡ ጥሩ ፡ ዕጣን ፡ አድርግ ። በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ሁልጊዜ ፡ በሰንበት ፡ ቀን ፡ ሁሉ ፡ በተርታ ፡
ያድርገው ፤ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ የዘላ
፱ ለም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ነው ። ለአሮንና ፡ ለልጆ
ቹም ፡ ይሁን ፤ በእሳት ፡ ከተደረገው ፡ ከእግዚ
አብሔር ፡ ቍርባን ፡ በዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ለእ
ርሱ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱሳን ፡ ነውና ፡ በተቀደሰ ፡ ስፍራ ፡
ይብሉት ።

፲ አባቱ ፡ ግብፃዊ ፡ የነበረ ፡ የእስራኤላዊት ፡
ልጅ ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ወጣ ፤
የእስራኤላዊቱ ፡ ልጅና ፡ አንድ ፡ እስራኤላዊ ፡
፲፩ በሰፈር ፡ ውስጥ ፡ ተጣሉ ፤ የእስራኤላዊቱም ፡
ልጅ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ሰደበ ፥ አቃለ
ለውም ፤ ወደ ፡ ሙሴም ፡ አመጡት ። እናቱም ፡
ከዳን ፡ ነገድ ፡ የደብራይ ፡ ልጅ ፡ ነበረች ፥ ስም
፲፪ ዋም ፡ ሰሎሚት ፡ ነበረ ። ከእግዚአብሔርም ፡
አፍ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ፍርድ ፡ እስኪወጣላቸው ፡
ድረስ ፡ በግዞት ፡ አኖሩት ።

፲፫ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፲፬ ተናገረው ፦ ተሳዳቢውን ፡ ከሰፈሩ ፡ ወደ ፡
ውጭ ፡ አውጣው ፤ የሰሙትም ፡ ሁሉ ፡ እጃቸ
ውን ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ይጫኑበት ፤ ማኅበሩም ፡
፲፭ ሁሉ ፡ ይውገረው ። ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እን
ዲህ ፡ ብለህ ፡ ትነግራለህ ፦ ማናቸውም ፡ ሰው ፡
አምላኩን ፡ ቢሰድብ ፡ ኃጢአቱን ፡ ይሸከማል ።
፲፮ የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ የሚሰድብ ፡ ፈጽሞ ፡
ይገደል ፤ ማኅበሩም ፡ ሁሉ ፡ ይውገሩት ፤
መጻተኛ ፡ ወይም ፡ የአገር ፡ ልጅ ፡ ቢሆን ፥
የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ በሰደበ ፡ ጊዜ ፡ ይገ
፲፯ ደል ። ሰውንም ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ የሚ
፲፰ መታ ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደል ። እንስሳንም ፡ እስኪ
ሞት ፡ ድረስ ፡ የሚመታ ፡ ሕይወት ፡ በሕይወት ፡
፲፱ ፋንታ ፡ ካሣውን ፡ ይክፈል ። ሰውም ፡ ባልንጀ
ራውን ፡ ቢጎዳ ፥ እርሱ ፡ እንዳደረገ ፡ እንዲሁ ፡
፳ ይደረግበት ። ስብራት ፡ በስብራት ፡ ፋንታ ፥
ዓይን ፡ በዓይን ፡ ፋንታ ፥ ጥርስ ፡ በጥርስ ፡ ፋንታ ፥
ሰውን ፡ እንደ ፡ ጐዳ ፡ እንዲሁ ፡ ይደረግበት ።
፳፩ እንስሳውንም ፡ የሚገድል ፡ ካሣ ፡ ይተካ ፤ ሰው
፳፪ ንም ፡ የሚገድል ፡ ይገደል ። እኔ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝና ፡ ለመጻተኛና ፡ ለአገር ፡
ልጅ ፡ አንድ ፡ ዓይነት ፡ ሕግ ፡ ይሁንላችሁ ።
፳፫ ሙሴም ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተናገራቸው ፤
ተሳዳቢውንም ፡ ከሰፈሩ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አወ
ጡት ፥ በድንጋይም ፡ ወገሩት ። የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡
አደረጉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ በሲና ፡ ተራራ ፡
፪ ላይ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፦ ለእስራኤል ፡
ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፦ እኔ ፡ ወደም
ሰጣችሁ ፡ ምድር ፡ በገባችሁ ፡ ጊዜ ፡ ምድሪቱ ፡
፫ ለእግዚአብሔር ፡ ሰንበት ፡ ታድርግ ። ስድስት ፡
ዓመት ፡ እርሻህን ፡ ዝራ ፥ ስድስት ፡ ዓመትም ፡
፬ ወይንህን ፡ ቍረጥ ፡ ፍሬዋንም ፡ አግባ ። በሰባ
ተኛው ፡ ዓመት ፡ ግን ፡ ለምድሪቱ ፡ የዕረፍት ፡
ሰንበት ፥ ለእግዚአብሔር ፡ ሰንበት ፥ ትሁን ፤
እርሻህን ፡ አትዝራ ፥ ወይንህንም ፡ አትቍረጥ ።
፭ የምድራችሁን ፡ የገቦ ፡ አትጨደው ፥ ያልተቈ
ረጠውንም ፡ የወይንህን ፡ ፍሬ ፡ አታከማች ፤
ለምድሪቱ ፡ የዕረፍት ፡ ሰንበት ፡ ዓመት ፡ ይሁን ።
፮ የምድርም ፡ ሰንበት ፡ ለአንተ ፥ ለወንድ ፡ ባሪ
ያህም ፥ ለሴት ፡ ባሪያህም ፥ ለምንደኛም ፥ ከአ
ንተ ፡ ጋር ፡ ለሚኖር ፡ ለመጻተኛም ፡ ምግብ ፡
፯ ይሁን ። ለእንስሶችህም ፥ በምድርህም ፡ ላሉት ፡
አራዊት ፡ ፍሬዋ ፡ ሁሉ ፡ መኖ ፡ ይሁን ።

፰ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ሰባት ፡ አድርገህ ፡ የዓመታትን ፡
ሰንበት ፡ ሰባት ፡ ቍጠር ፤ የሰባት ፡ ዓመታትም ፡
ሰንበት ፡ ዘመን ፡ አርባ ፡ ዘጠኝ ፡ ዓመት ፡ ትቈ
፱ ጥራለህ ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ በሰባተኛው ፡ ወር ፡
በአሥረኛው ፡ ቀን ፡ በቀንደ ፡ መለከት ፡ ታውጃ
ለህ ፤ በማስተስረያ ፡ ቀን ፡ በምድራችሁ ፡ ሁሉ ፡
፲ በቀንደ ፡ መለከት ፡ ታውጃላችሁ ። አምሳኛ
ውንም ፡ ዓመት ፡ ትቀድሳላችሁ ፥ በምድሪቱም ፡
ለሚኖሩበት ፡ ሁሉ ፡ ነጻነትን ፡ ታውጃላችሁ ፤
እርሱ ፡ ለእናንተ ፡ ኢዮቤልዩ ፡ ነው ፤ ሰው ፡
ሁሉ ፡ ወደ ፡ ርስቱና ፡ ወደ ፡ ወገኑ ፡ ይመለስ ።
፲፩ ያ ፡ አምሳኛው ፡ ዓመት ፡ ለእናንተ ፡ ኢዮቤልዩ ፡
ይሆናል ፤ በእርሱም ፡ አትዝሩ ፥ የገቦውንም ፡
አትጨዱ ፥ የወይኑንም ፡ ፍሬ ፡ አታከማቹ ።
፲፪ ኢዮቤልዩ ፡ ነውና ፡ የተቀደሰ ፡ ይሁንላችሁ ፤
በሜዳ ፡ ላይ ፡ የበቀለውን ፡ ብሉ ።

፲፫ በዚች ፡ በኢዮቤልዩ ፡ ዓመት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡
፲፬ ወደ ፡ ርስቱ ፡ ይመለሳል ። ለባልንጀራህም ፡
አንዳች ፡ ብትሸጥለት ፥ ወይም ፡ ከባልንጀራህ ፡
እጅ ፡ ብትገዛ ፥ ሰው ፡ ባልንጀራውን ፡ አያታ
፲፭ ልል ። ከኢዮቤልዩ ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ዓመታቱ ፡
ቍጥር ፡ ከባልንጀራህ ፡ ትገዛለህ ፤ እርሱም ፡
እንደ ፡ መከሩ ፡ ዓመታት ፡ ቍጥር ፡ ይሸጥልሃል ።
፲፮ እንደ ፡ ዓመታቱ ፡ ብዛት ፡ ዋጋውን ፡ ታበዛለህ ፥
እንደ ፡ ዓመታቱም ፡ ማነስ ፡ ዋጋውን ፡ ታሳንሳ
ለህ ፤ እንደ ፡ መከሩ ፡ ቍጥር ፡ ይሸጥልሃል ።
፲፯ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝና ፡
ሰው ፡ ባልንጀራውን ፡ አያታልል ፥ ነገር ፡ ግን ፡
አምላክህን ፡ ፍራ ።

፲፰ ሥርዓቴንም ፡ አድርጉ ፥ ፍርዶቼንም ፡ ጠብቁ ፡

አድርጉትም ፤ በምድሪቱም ፡ ውስጥ ፡ በጸጥታ ፡
፲፱ ትኖራላችሁ ። ምድሪቱም ፡ ፍሬዋን ፡ ትሰጣ
ለች ፥ እስክትጠግቡም ፡ ድረስ ፡ ትበላላችሁ ፤
በእርስዋም ፡ ውስጥ ፡ በጸጥታ ፡ ትኖራላችሁ ።
፳ እናንተም ፡— ካልዘራን ፥ እህላችንንም ፡ ካላከ
ማቸን ፡ በሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ ምን ፡ እንበላ
፳፩ ለን ? ብትሉ ፥ እኔ ፡ በስድስተኛው ፡ ዓመት ፡
በረከቴን ፡ በላያችሁ ፡ አዝዛለሁ ፤ ምድሪቱም ፡
፳፪ የሦስት ፡ ዓመት ፡ ፍሬ ፡ ታፈራለች ። በስምንተ
ኛውም ፡ ዓመት ፡ ትዘራላችሁ ፥ ከአሮጌውም ፡
እህል ፡ ትበላላችሁ ፤ ፍሬዋ ፡ እስኪገባ ፥ እስከ ፡
ዘጠነኛው ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፥ ከአሮጌው ፡ እህል ፡
ትበላላችሁ ።

፳፫ ምድርም ፡ ለእኔ ፡ ናትና ፥ እናንተም ፡ ከእኔ ፡
ጋር ፡ እንግዶችና ፡ መጻተኞች ፡ ናችሁና ፡ ምድ
፳፬ ርን ፡ ለዘላለም ፡ አትሽጡ ። በርስታችሁም ፡
ምድር ፡ ሁሉ ፡ መቤዠትን ፡ ለምድሪቱ ፡ አድ
፳፭ ርጉ ። ወንድምህም ፡ ቢደኸይ ፡ ከርስቱም ፡ ቢሸጥ ፥
ለእርሱ ፡ የቀረበ ፡ ዘመዱ ፡ መጥቶ ፡ ወንድሙ ፡ የሸ
፳፮ ጠውን ፡ ይቤዠዋል ። የሚቤዠውም ፡ ሰው ፡
ቢያጣ ፥ እርሱም ፡ እጁ ፡ ቢረጥብ ፥ ለመቤዠ
፳፯ ትም ፡ የሚበቃ ፡ ቢያገኝ ፥ የሽያጩን ፡ ዘመን ፡
ቈጥሮ ፡ የቀረውን ፡ ወደ ፡ ገዛው ፡ ሰው ፡ ይመ
፳፰ ልስ ፤ እርሱም ፡ ወደ ፡ ርስቱ ፡ ይመለስ ። ለራ
ሱም ፡ ዕዳውን ፡ መክፈል ፡ ባይችል ፥ ሽያጩ ፡
በገዛው ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ እስከ ፡ ኢዮቤልዩ ፡ ዓመት ፡
ድረስ ፡ ይቀመጥ ፤ በኢዮቤልዩም ፡ ዓመት ፡
ይውጣ ፥ እርሱም ፡ ወደ ፡ ርስቱ ፡ ይመለስ ።

፳፱ ሰውም ፡ ቅጥር ፡ ባለበት ፡ ከተማ ፡ መኖሪያ ፡
ቤትን ፡ ቢሸጥ ፥ ከተሸጠ ፡ በኋላ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡
እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ ለመቤዠት ፡ ይችላል ፤
ለአንድ ፡ ሙሉ ፡ ዓመት ፡ መቤዠት ፡ ይችላል ።
፴ አንድ ፡ ዓመትም ፡ እስኪጨረስ ፡ ባይቤዠው ፥
ቅጥር ፡ ባለበት ፡ ከተማ ፡ የሚሆን ፡ ቤት ፡ ለገ
ዛው ፡ ለልጅ ፡ ልጁ ፡ ለዘላለም ፡ ይጸናለታል ፤
፴፩ በኢዮቤልዩም ፡ ከእርሱ ፡ አይወጣም ። ቅጥር ፡
በሌለበት ፡ መንደር ፡ ያሉ ፡ ቤቶች ፡ ግን ፡ እንደ ፡
እርሻ ፡ ይቈጠራሉ ፤ ይቤዠሉ ፥ በኢዮቤል
፴፪ ዩም ፡ ይወጣሉ ። በእነርሱ ፡ ከተማ ፡ ያለ ፡ የሌ
ዋውያን ፡ ቤት ፡ ግን ፡ ሌዋውያን ፡ ለዘላለም ፡
፴፫ መቤዠት ፡ ይችላሉ ። ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ከሌ
ዋውያን ፡ ቢገዛ ፥ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካ
ከል ፡ የሌዋውያን ፡ ከተማ ፡ ቤቶች ፡ ርስቶቻ
ቸው ፡ ናቸውና ፡ በርስቱ ፡ ከተማ ፡ ያለ ፡ የተሸ
፴፬ ጠው ፡ ቤት ፡ በኢዮቤልዩ ፡ ይመለሳል ። በከ
ተማቸውም ፡ ዙሪያ ፡ ያለችው ፡ መሰምርያ ፡ የዘ
ላለም ፡ ርስታቸው ፡ ናትና ፡ አትሸጥም ።

፴፭ ወንድምህ ፡ ቢደኸይ ፡ እጁም ፡ በአንተ ፡
ዘንድ ፡ ቢደክም ፥ አጽናው ፤ እንደ ፡ እንግዳና ፡
እንደ ፡ መጻተኛም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይኑር ።
፴፮ ወንድምህ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ ከእ
ርሱ ፡ ምንም ፡ ወለድ ፡ ወይም ፡ ትርፍ ፡ አትው
፴፯ ሰድ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አምላክህን ፡ ፍራ ። ብር
ህን ፡ በወለድ ፡ አታበድረው ፤ መኖህንም ፡ በት
ርፍ ፡ አትስጠው ። የከነዓንን ፡ ምድር ፡ እሰጣ ፴፰
ችሁ ፡ ዘንድ ፥ አምላክም ፡ እሆናችሁ ፡ ዘንድ ፡
ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣኋችሁ ፡ እኔ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝ ።

፴፱ ወንድምህም ፡ ቢደኸይ ፡ ራሱንም ፡ ለአንተ ፡
ቢሸጥ ፥ እንደ ፡ ባሪያ ፡ አድርገህ ፡ አትግዛው ።
፵ እንደ ፡ ምንደኛና ፡ እንደ ፡ መጻተኛ ፡ ከአንተ ፡
ጋር ፡ ይሁን ፤ እስከ ፡ ኢዮቤልዩም ፡ ዓመት ፡
፵፩ ያገልግልህ ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ እርሱ ፡ ከል
ጆቹ ፡ ጋር ፡ ከአንተ ፡ ይውጣ ፥ ወደ ፡ ወገኖ
፵፪ ቹም ፡ ወደ ፡ አባቱም ፡ ርስት ፡ ይመለስ ። ከግ
ብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣኋቸው ፡ ባሪያዎቼ ፡ ናቸ
፵፫ ውና ፡ እንደ ፡ ባሪያዎች ፡ አይሸጡ ። በጽኑ ፡
እጅ ፡ አትግዛው ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አምላክህን ፡
፵፬ ፍራ ። ወንድ ፡ ባሪያና ፡ ሴት ፡ ባሪያ ፡ መግዛት ፡
ብትፈልግ ፡ ግን ፡ በዙሪያችሁ ፡ ካሉት ፡ ከእነ
ርሱ ፡ ከአሕዛብ ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ ባሪያዎችን ፡
፵፭ ግዙ ። ደግሞም ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡ ከሚ
ቀመጡት ፡ መጻተኞች ፥ በምድራችሁም ፡
ውስጥ ፡ ከወለዱአቸው ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡
ከሚቀመጡት ፡ ከዘራቸው ፡ ውስጥ ፡ ባሪያዎ
፵፮ ችን ፡ ግዙ ፤ ርስትም ፡ ይሁኑላችሁ ። ከእናን
ተም ፡ በኋላ ፡ ልጆቻችሁ ፡ ይወርሱአቸው ፡
ዘንድ ፡ ተዉአቸው ፤ ከእነርሱም ፡ ባሪያዎችን ፡
ለዘላለም ፡ ትወስዳላችሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የእስራ
ኤልን ፡ ልጆች ፡ ወንድሞቻችሁን ፡ በጽኑ ፡
እጅ ፡ አትግዙአቸው ።

፵፯ በአንተም ፡ ዘንድ ፡ የሚኖር ፡ መጻተኛ ፡
ወይም ፡ እንግዳ ፡ ሀብታም ፡ ቢሆን ፥ ወንድም
ህም ፡ በእርሱ ፡ አጠገብ ፡ ቢደኸይ ፥ ራሱንም ፡
ለመጻተኛው ፡ ወይም ፡ ለእንግዳው ፡ ወይም ፡ ለወ
፵፰ ገኖቹ ፡ ዘር ፡ ቢሸጥ ፥ ከተሸጠ ፡ በኋላ ፡ መቤ
ዠት ፡ ይችላል ፤ ከወንድሞቹ ፡ አንዱ ፡ ይቤ
፵፱ ዠው ፤ ወይም ፡ አጎቱ ፡ ወይም ፡ የአጎቱ ፡ ልጅ ፡
ይቤዠው ፤ ወይም ፡ ከወገኑ ፡ ለእርሱ ፡ የቀ
ረበ ፡ ዘመድ ፡ ይቤዠው ፤ ወይም ፡ እርሱ ፡
፶ እጁ ፡ ቢረጥብ ፡ ራሱን ፡ ይቤዠው ። ከገዛውም ፡
ሰው ፡ ጋር ፡ ከገዛበት ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ኢዮቤልዩ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ይቍጠር ፤ የሽያ
ጩም ፡ ብር ፡ እንደ ፡ ዓመታቱ ፡ ቍጥር ፡ ይሁን ፤
እንደ ፡ ምንደኛውም ፡ ዘመን ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
፶፩ ይሁን ። ብዙ ፡ ዓመታትም ፡ ቢቀሩ ፡ እንደ ፡
እነርሱ ፡ ቍጥር ፡ ከሽያጩ ፡ ብር ፡ የመቤዠቱን ፡
፶፪ ዋጋ ፡ ይመልስ ። እስከ ፡ ኢዮቤልዩ ፡ ዓመት ፡
ድረስ ፡ ጥቂቶች ፡ ዓመታት ፡ ቢቀሩ ፡ ከእ
ርሱ ፡ ጋር ፡ ይቈጥራል ፤ እንደ ፡ ዓመታቱም ፡
መጠን ፡ የመቤዠቱን ፡ ዋጋ ፡ ይመልስ ።
፶፫ በየዓመቱ ፡ እንደ ፡ ምንደኛ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
ይኑር ፤ በፊትህ ፡ በጽኑ ፡ እጅ ፡ አይግዛው ።
፶፬ በዚህ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ባይቤዥ ፡ በኢዮ
ቤልዩ ፡ ዓመት ፡ እርሱ ፡ ከልጆቹ ፡ ጋር ፡ ይውጣ ።
፶፭ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ለእኔ ፡ ባሪያዎች ፡ ናቸ
ውና ፤ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣኋቸው ፡ ባሪያዎቼ ፡
ናቸው ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝና ፡
ለእናንተ ፡ ጣዖት ፡ አታድርጉ ፥ የተቀረጸም ፡
ምስል ፡ ወይም ፡ ሐውልት ፡ አታቁሙ ፤ ትሰግ
ዱለትም ፡ ዘንድ ፡ በምድራችሁ ፡ ላይ ፡ የተቀ
፪ ረጸ ፡ ድንጋይ ፡ አታኑሩ ። ሰንበታቴን ፡ ጠብቁ ፥
መቅደሴንም ፡ ፍሩ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ።
፫ በሥርዓቴ ፡ ብትሄዱ ፥ ትእዛዛቴንም ፡ ብትጠ
፬ ብቁ ፡ ብታደርጉትም ፥ ዝናባችሁን ፡ በወቅቱ ፡
አዘንባለሁ ፥ ምድሪቱም ፡ እህልዋን ፡ ትሰጣ
ለች ፥ የሜዳው ፡ ዛፎችም ፡ ፍሬአቸውን ፡ ይሰ
፭ ጣሉ ። የእህሉም ፡ ማበራየት ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡
እስከ ፡ ወይኑ ፡ መቍረጥ ፡ ይደርሳል ፥ የወይ
ኑም ፡ መቍረጥ ፡ እስከ ፡ እህሉ ፡ መዝራት ፡ ይደ
ርሳል ፤ እስክትጠግቡም ፡ ድረስ ፡ እንጀራች
ሁን ፡ ትበላላችሁ ፥ በምድራችሁም ፡ ላይ ፡ በጸ
፮ ጥታ ፡ ትኖራላችሁ ። በምድራችሁም ፡ ላይ ፡
ሰላምን ፡ እሰጣለሁ ፥ ማንም ፡ ሳያስፈራችሁ ፡
ትተኛላችሁ ፤ ክፉዎችንም ፡ አራዊት ፡ ከምድ
ራችሁ ፡ አጠፋለሁ ፥ ሰይፍም ፡ በምድራችሁ ፡
፯ ላይ ፡ አያልፍም ። ጠላቶቻችሁንም ፡ ታሳድዳ
ላችሁ ፥ በፊታችሁም ፡ በሰይፍ ፡ ይወድቃሉ ።
፰ ከእናንተም ፡ አምስቱ ፡ መቶውን ፡ ያሳድዳሉ ፥
መቶውም ፡ አሥሩን ፡ ሺህ ፡ ያሳድዳሉ ፤ ጠላቶ
ቻችሁም ፡ በፊታችሁ ፡ በሰይፍ ፡ ይወድቃሉ ።
፱ ፊቴም ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ይሆናል ፥ እንድታፈሩም ፡
አደርጋችኋለሁ ፥ አበዛችሁማለሁ ፤ ቃል ፡ ኪዳ
፲ ኔንም ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ አጸናለሁ ። ብዙ ፡ ጊዜ ፡
የተቀመጠውንም ፡ አሮጌውን ፡ እህል ፡ ትበላላ
ችሁ ፤ ከአዲሱም ፡ በፊት ፡ አሮጌውን ፡ ታወጣ
፲፩ ላችሁ ። ማደሪያዬንም ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡
፲፪ አደርጋለሁ ፤ ነፍሴም ፡ አትጸየፋችሁም ። በመ
ካከላችሁም ፡ እሄዳለሁ ፥ እኔም ፡ አምላክ ፡ እሆ
ናችኋለሁ ፥ እናንተም ፡ ሕዝብ ፡ ትሆኑኛላችሁ ።
፲፫ ባሪያዎች ፡ እንዳትሆኑአቸው ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡
ያወጣኋችሁ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡
ነኝ ፤ የበርነታችሁን ፡ ቀንበር ፡ ሰብሬአለሁ ፤ ቀና ፡
ብላችሁ ፡ እንድትሄዱ ፡ አድርጌአችኋለሁ ።
፲፬ ነገር ፡ ግን ፡ ባትሰሙኝ ፥ እነዚህንም ፡ ትእዛ
፲፭ ዛት ፡ ሁሉ ፡ ባታደርጉ ፥ ሥርዓቴንም ፡ ብትንቁ ፥
ትእዛዛቴንም ፡ ሁሉ ፡ እንዳታደርጉ ፥ ቃል ፡ ኪዳ
ኔንም ፡ እንድታፈርሱ ፡ ነፍሳችሁ ፡ ፍርዴን ፡
፲፮ ብትጸየፍ ፥ እኔም ፡ እንዲህ ፡ አደርግባችኋለሁ ፤
ፍርሃትን ፥ ክሳትንም ፥ ዓይናችሁንም ፡ የሚያፈ
ዝዝ ፥ ሰውነታችሁንም ፡ የሚያማስን ፡ ትኩሳት ፡
አወርድባችኋለሁ ፤ ዘራችሁንም ፡ በከንቱ ፡ ትዘ
፲፯ ራላችሁ ፥ ጠላቶቻችሁ ፡ ይበሉታልና ። ፊቴ
ንም ፡ አከብድባችኋለሁ ፥ በጠላቶቻችሁም ፡
ፊት ፡ ትወድቃላችሁ ፤ የሚጠሉአችሁም ፡ ይገዙ
አችኋል ፤ ማንም ፡ ሳያሳድዳችሁ ፡ ትሸሻላችሁ ።
፲፰ እስከዚህም ፡ ድረስ ፡ ባትሰሙኝ ፥ ስለ ፡ ኃጢአ
ታችሁ ፡ በቅጣታችሁ ፡ ላይ ፡ ሰባት ፡ እጥፍ ፡ እጨ
፲፱ ምራለሁ ። የኃይላችሁንም ፡ ትዕቢት ፡ እሰብ
ራለሁ ፤ ሰማያችሁንም ፡ እንደ ፡ ብረት ፥ ምድራ
ችሁንም ፡ እንደ ፡ ናስ ፡ አደርጋለሁ ። ጕልበታ ፳
ችሁም ፡ በከንቱ ፡ ያልቃል ፤ ምድራችሁም ፡
እህልዋን ፡ አትሰጥም ፥ የምድርም ፡ ዛፎች ፡
ፍሬአቸውን ፡ አይሰጡም ።
፳፩ በእንቢተኝነትም ፡ ብትሄዱብኝ ፡ ባትሰሙ
ኝም ፥ እንደ ፡ ኃጢአታችሁ ፡ መጠን ፡ በመቅ
ሠፍት ፡ ላይ ፡ ሰባት ፡ እጥፍ ፡ እጨምራለሁ ።
፳፪ በመካከላችሁም ፡ የምድርን ፡ አራዊት ፡ እሰድዳ
ለሁ ፤ ልጆቻችሁንም ፡ ይነጥቃሉ ፥ እንስሶቻ
ችሁንም ፡ ያጠፋሉ ፥ እናንተንም ፡ ያሳንሳሉ ፤
መንገዶቻችሁም ፡ በረሀ ፡ ይሆናሉ ።
፳፫ እስከዚህም ፡ ድረስ ፡ ባትቀጡ ፥ በእንቢተኝ
፳፬ ነትም ፡ ብትሄዱ ፥ እኔ ፡ ደግሞ ፡ በእንቢተኝ
ነት ፡ እሄድባችኋለሁ ፤ ስለ ፡ ኃጢአታችሁም ፡
፳፭ ሰባት ፡ እጥፍ ፡ እመታችኋለሁ ። የቃል ፡ ኪዳ
ኔንም ፡ በቀል ፡ ይበቀልባችሁ ፡ ዘንድ ፡ ሰይፍ ፡
አመጣባችኋለሁ ፤ ወደ ፡ ከተማችሁም ፡ ትሰበሰ
ባላችሁ ፥ ቸነፈርንም ፡ እሰድድባችኋለሁ ፤ በጠ
፳፮ ላትም ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣችኋለሁ ። የእህ
ላችሁንም ፡ ድጋፍ ፡ በሰበርሁ ፡ ጊዜ ፥ አሥር ፡
ሴቶች ፡ እንጀራቸውን ፡ በአንድ ፡ ምጣድ ፡ ይጋ
ግራሉ ፥ በሚዛንም ፡ መዝነው ፡ እንጀራችሁን ፡
ይመልሱላችኋል ፤ በበላችሁም ፡ ጊዜ ፡ አትጠ
ግቡም ።
፳፯ እስከዚህም ፡ ድረስ ፡ ባትሰሙኝ ፥ በእንቢተ
፳፰ ኝነትም ፡ ብትሄዱብኝ ፥ እኔ ፡ ደግሞ ፡ በቍጣ ፡
እሄድባችኋለሁ ፤ ስለ ፡ ኃጢአታችሁም ፡ ሰባት ፡
፳፱ እጥፍ ፡ እቀጣችኋለሁ ። የወንዶች ፡ ልጆቻች
ሁንም ፡ ሥጋ ፡ ትበላላችሁ ፤ የሴቶች ፡ ልጆቻ
፴ ችሁንም ፡ ሥጋ ፡ ትበላላችሁ ። የኮረብታ ፡ መስ
ገጃዎቻችሁንም ፡ አፈርሳለሁ ፥ የፀሐይ ፡ ምስ
ሎቻችሁንም ፡ አጠፋለሁ ፥ ሬሳችሁንም ፡ በጣ
ዖቶቻችሁ ፡ ሬሳዎች ፡ ላይ ፡ እጥላለሁ ፤ ነፍሴም ፡
፴፩ ትጸየፋችኋለች ። ከተሞቻችሁንም ፡ በድማ ፡
አደርጋለሁ ፥ መቅደሶቻችሁንም ፡ አፈርሳለሁ ፥
፴፪ መልካሙንም ፡ መዓዛችሁን ፡ አላሸትትም ። ምድ
ሪቱንም ፡ የተፈታች ፡ አደርጋለሁ ፤ የሚቀመጡ
ባት ፡ ጠላቶቻችሁም ፡ በእርስዋ ፡ የተነሣ ፡ ይደ
፴፫ ነቃሉ ። እናንተንም ፡ ከአሕዛብ ፡ መካከል ፡ እበ
ትናችኋለሁ ፥ ሰይፍንም ፡ እስመዝዝባችኋለሁ ፤
ምድራችሁም ፡ የተፈታች ፡ ትሆናለች ፥ ከተሞ
ቻችሁም ፡ በድማ ፡ ይሆናሉ ።
፴፬ በዚያም ፡ በተፈታችበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡
እናንተም ፡ በጠላቶቻችሁ ፡ ምድር ፡ ሳላችሁ ፥
ምድሪቱ ፡ ሰንበት ፡ በማድረግዋ ፡ ትደሰታለች ፤
በዚያም ፡ ጊዜ ፡ ምድሪቱ ፡ ታርፋለች ፥ ሰንበ
፴፭ ትንም ፡ በማድረግዋ ፡ ትደሰታለች ። እናንተ ፡
ተቀምጣችሁባት ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፡ በሰንበቶቻችሁ ፡
አላረፈችም ፡ ነበርና ፡ በተፈታችበት ፡ ዘመን ፡
፴፮ ሁሉ ፡ ታርፋለች ። በጠላቶቻቸውም ፡ ምድ
ሮች ፡ ሳሉ ፡ ከእናንተ ፡ ተለይተው ፡ በቀሩት ፡
ላይ ፡ በልባቸው ፡ ድንጋጤን ፡ እሰድድባቸዋለሁ ፤
በነፋስም ፡ የምትንቀሳቀስ ፡ የቅጠል ፡ ድምፅ ፡

ታሸብሩቸዋለች ፤ ከሰይፍ፡እንደሚሸሹ፡ይሸሻሉ ፤ ማንም ፡ ሳያሳድዳቸው ፡ ይወድቃሉ ። ፴፯ ማንም ፡ ሳያሳድዳቸው ፡ ከሰይፍ ፡ እንዲሸሹ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ይሰነካከላሉ ፤ እናንተም ፡ በጠላቶቻችሁ ፡ ፊት ፡ መቆም ፡ አትችሉም ። ፴፰ በአሕዛብም ፡ መካከል ፡ ታልቃላችሁ ፥ የጠላ ፴፱ ቶቻችሁም ፡ ምድር ፡ ትውጣችኋለች ። ከእናንተም ፡ ተለይተው ፡ የቀሩት ፡ በጠላቶቻቸው ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ በኃጢአታቸው ፡ ይከሳሉ ፤ በአባቶቻቸውም ፡ ኃጢአት ፡ ደግሞ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ይከሳሉ ።

፵ በእኔም ፡ ላይ ፡ በእንቢተኝነት ፡ ስለ ፡ ሄዱብኝ ፡ የበደሉኝን ፡ በደል ፥ ኃጢአታቸውንም ፥ የአባቶቻቸውንም ፡ ኃጢአት ፡ ይናዘዛሉ ። ፵፩ እኔም ፡ ደግሞ ፡ በእንቢተኝነት ፡ ሄድሁባቸው ፤ ወደ ፡ ጠላቶቻቸውም ፡ ምድር ፡ አገባኋቸው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ያልተገረዘው ፡ ልባቸው ፡ ቢዋረድ ፥ የኃጢአታቸውንም ፡ ቅጣት ፡ ፵፪ ቢቀበሉ ፥ እኔ ፡ ለያዕቆብ ፡ የማልሁትን ፡ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ አስባለሁ ፤ ደግሞ ፡ ለይስሐቅና ፡ ለአብርሃም ፡ የማልሁትን ፡ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ አስባ ፵፫ ለሁ ፤ ምድሪቱንም ፡ አስባለሁ ። ምድርም ፡ ከእነርሱ ፡ መጥፋት ፡ የተነሣ ፡ ባዶ ፡ ትቀራለች ፤ እነርሱም ፡ ሳይኖሩ ፡ በተፈታችበት ፡ ዘመን ፡ ሰንበት ፡ በማድረግዋ ፡ ትደሰታለች ፤ ፍርዴንም ፡ ስለ ፡ ናቁ ፥ ነፍሳቸውም ፡ ሥርዓቴን ፡ ስለ ፡ ተጸየፈች ፡ የኃጢአታቸውን ፡ ቅጣት ፡ ፵፬ ይሸከማሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካቸው ፡ ነኝና ፡ እነርሱ ፡ በጠላቶቻቸው ፡ ምድር ፡ ሳሉ ፥ እስከጠፋቸው ፡ ድረስ ፡ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ያለኝን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ እስከፈርስ ፡ ድረስ ፡ አልጥላቸውም ፡ አልጸየፋቸውምም ። ፵፭ እኔ ፡ አምላካቸው ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ አሕዛብ ፡ እያዩ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣኋቸውን ፡ የአባቶቻቸውን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ አስባለሁ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ።

፵፮ እግዚአብሔርም ፡ በእርሱና ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ በሲና ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ ያደረጋቸው ፡ ሥርዓቶችና ፡ ፍርዶች ፡ ሕግጋትም ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

፩ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፪ ተናገረው ፦ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፦ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ሰውን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሊሰጥ ፡ ቢሳል ፡ አንተ ፡ እንደምትገምተው ፡ መጠን ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ዋጋውን ፡ ፫ ይስጥ ። ለወንድ ፡ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ስድሳ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ ግምቱ ፡ አምሳ ፡ የብር ፡ ፬ ሰቅል ፡ ይሁን ። ሴትም ፡ ብትሆን ፡ ግምትዋ ፡ ፭ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡ ይሁን ። ከአምስት ፡ ዓመትም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሀያ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ግምቱ ፡ ለወንድ ፡ ሀያ ፡ ሰቅል ፥ ለሴትም ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ ይሁን ። ፮ ከአንድ ፡ ወርም ፡ እስከ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ለወንድ ፡ ግምቱ ፡ አምስት ፡ የብር ፡ ሰቅል ፥ ለሴትም ፡ ግምትዋ ፡ ሦስት ፡ የብር ፡ ሰቅል ፡ ይሁን ። ፯ ከስድሳ ፡ ዓመትም ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ወንድ ፡ ቢሆን ፡ ግምቱ ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡ ሰቅል ፥ ለሴትም ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ ይሁን ። ፰ ለግምቱም ፡ የሚከፍለውን ፡ ቢያጣ ፡ ግን ፡ በካህኑ ፡ ፊት ፡ ይቁም ፥ ካህኑም ፡ የተሳለውን ፡ ሰው ፡ ይገምተው ፤ ካህኑም ፡ የተሳለው ፡ ሰው ፡ እንደሚችል ፡ መጠን ፡ ይገምተው ።

፱ ለእግዚአብሔርም ፡ መሥዋዕት ፡ አድርገው ፡ የሚያቀርበው ፡ እንስሳ ፡ ቢሆን ፥ ሰው ፡ ከእነዚህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚሰጠው ፡ ሁሉ ፡ ቅዱስ ፡ ይሆናል ። ፲ መልካሙን ፡ በክፉ ፥ ክፉውንም ፡ በመልካም ፡ አይለውጥ ፤ እንስሳንም ፡ በእንስሳ ፡ ቢለውጥ ፡ እርሱና ፡ ልዋጩ ፡ የተቀደሱ ፡ ይሆናሉ ። ፲፩ እንስሳው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሥዋዕት ፡ መሆን ፡ የማይገባው ፡ ርኩስ ፡ ቢሆን ፥ እንስሳውን ፡ በካህኑ ፡ ፊት ፡ ያኑረው ። ፲፪ መልካምም ፡ ቢሆን ፡ ክፉም ፡ ቢሆን ፡ ካህኑ ፡ ይገምተው ፤ ካህኑም ፡ እንደሚገምተው ፡ መጠን ፡ እንዲሁ ፡ ይሁን ። ፲፫ ይቤዠውም ፡ ዘንድ ፡ ቢወድድ ፡ ከግምቱ ፡ በላይ ፡ አምስተኛ ፡ ይጨምር ።

፲፬ ሰውም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቅዱስ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ቤቱን ፡ ቢቀድስ ፥ ካህኑ ፡ መልካም ፡ ወይም ፡ ክፉ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይገምተዋል ፤ ካህኑም ፡ እንደሚገምተው ፡ መጠን ፡ እንዲሁ ፡ ይቆማል ። ፲፭ የቀደሰውም ፡ ሰው ፡ ቤቱን ፡ ይቤዠው ፡ ዘንድ ፡ ቢወድድ ፡ ከግምቱ ፡ ገንዘብ ፡ በላይ ፡ አምስተኛ ፡ ይጨምር ፤ ቤቱም ፡ ለእርሱ ፡ ይሆናል ።

፲፮ ሰውም ፡ ከርስቱ ፡ እርሻ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቢቀድስ ፥ እንደ ፡ መዘሪቱ ፡ መጠን ፡ ይገመት ፤ አንድ ፡ የቆሮስ ፡ መስፈሪያ ፡ ገብስ ፡ የሚዘራበት ፡ እርሻ ፡ አምሳ ፡ የብር ፡ ሰቅል ፡ ይገመታል ። ፲፯ እርሻውንም ፡ ከኢዮቤልዩ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ቢቀድስ ፥ እንደ ፡ ግምቱ ፡ መጠን ፡ ይቆማል ። ፲፰ እርሻውንም ፡ ከኢዮቤልዩ ፡ ዓመት ፡ በኋላ ፡ ቢቀድስ ፥ ካህኑ ፡ እስከ ፡ ኢዮቤልዩ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ ቀሩት ፡ ዓመታት ፡ ገንዘቡን ፡ ይቈጥርለታል ፤ ከግምቱም ፡ ይጐድላል ። ፲፱ እርሻውንም ፡ የቀደሰ ፡ ሰው ፡ ይቤዠው ፡ ዘንድ ፡ ቢወድድ ፥ ከግምቱ ፡ ገንዘብ ፡ በላይ ፡ አምስተኛ ፡ ይጨምር ፤ ለእርሱም ፡ ይሆናል ። ፳ እርሻውንም ፡ ባይቤዠው ፥ ወይም ፡ ለሌላ ፡ ሰው ፡ ቢሸጥ ፥ እንደ ፡ ገና ፡ ይቤዠው ፡ ዘንድ ፡ አይቻለውም ። ፳፩ እርሻው ፡ ግን ፡ በኢዮቤልዩ ፡ ሲወጣ ፡ እንደ ፡ እርም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ ፡ እርሻ ፡ ይሆናል ፤ ርስቱ ፡ ለካህኑ ፡ ይሆናል ። ፳፪ ከርስቱ ፡ እርሻ ፡ ያልሆነውን ፡ የገዛውን ፡ እርሻ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቢቀድስ ፥ ፳፫ ካህኑ ፡ እስከ ፡ ኢዮቤልዩ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ የግምቱን ፡ ዋጋ ፡ ይቈጥርለታል ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ግምቱን ፡ እንደ ፡ ተቀደሰ ፡ ነገር ፡

፳፬፤ ለእግዚአብሔር ፡ ይሰጣል ። በኢዮቤልዩ ፡
ዓመት ፡ እርሻው ፡ የምድሪቱ ፡ ባለ ፡ ርስት ፡ ወደ ፡
ነበረው ፡ ወደ ፡ ሸጠው ፡ ሰው ፡ ይመለሳል ።
፳፭፤ ግምቱም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡
ሚዛን ፡ ይሆናል ፤ ሰቅሉ ፡ ሀያ ፡ አቦሊ ፡ ይሆ
ናል ።
፳፮፤ ለእግዚአብሔር ፡ ግን ፡ የሚቀርበውን ፡ የእን
ስሳ ፡ በኵራት ፡ ማንም ፡ ይቀድሰው ፡ ዘንድ ፡ አይ
ቻለውም ፤ በሬ ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ በግ ፡ ለእግዚ
፳፯፤ አብሔር ፡ ነው ። የረከሰም ፡ እንስሳ ፡ ቢሆን ፡
እንደ ፡ ግምቱ ፡ ይቤዠው ፥ በእርሱም ፡ የዋ
ጋውን ፡ አምስተኛ ፡ ይጨምርበታል ፤ ባይቤ
ዥም ፡ እንደ ፡ ግምቱ ፡ ይሸጣል ።
፳፰፤ ለእግዚአብሔርም ፡ የተለየ ፡ እርም ፡ የሆነ ፡
ነገር ፡ ሁሉ ፥ ሰው ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ እንስሳ ፡
ወይም ፡ የርስቱ ፡ እርሻ ፡ ቢሆን ፥ አይሸጥም ፥
አይቤዥም ፤ እርም ፡ የሆነ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱሳን ፡ ነው ። ከሰዎ ፳፱፤
ችም ፡ እርም ፡ የሆነ ፡ ሁሉ ፡ አይቤዥም ፤ ፈጽሞ ፡
ይገደላል ።
፴፤ የምድርም ፡ አሥራት ፥ ወይም ፡ የምድር ፡
ዘር ፡ ወይም ፡ የዛፍ ፡ ፍሬ ፡ ቢሆን ፥ የእግዚአ
ብሔር ፡ ነው ፤ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ ፡ ነው ።
፴፩፤ ሰውም ፡ አሥራቱን ፡ ሊቤዥ ፡ ቢወድድ ፥ አም
፴፪፤ ስተኛ ፡ ይጨምርበታል ። ከበሬም ፡ ሁሉ ፡ ከአ
ሥር ፡ አንድ ፥ ከእረኛውም ፡ በትር ፡ በታች ፡
ከሚያልፍ ፡ በግና ፡ ፍየል ፡ ሁሉ ፡ ከአሥር ፡
አንድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ ፡ ይሆናል ።
፴፫፤ መልካም ፡ ወይም ፡ ክፉ ፡ እንዲሆን ፡ አይመር
ምር ፥ አይለውጥም ፤ ቢለውጠውም ፡ እርሱና ፡
ልዋጩ ፡ የተቀደሱ ፡ ይሆናሉ ፤ አይቤዠውም ።
፴፬፤ እግዚአብሔር ፡ በሲና ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ለእስ
ራኤል ፡ ልጆች ፡ ሙሴን ፡ ያዘዘው ፡ ትእዛዛት ፡
እነዚህ ፡ ናቸው ።

# ኦሪት ፡ ዘኍልቍ ።

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ በሲና ፡ ምድረ ፡
በዳ ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፥ በሁለተ
ኛው ፡ ወር ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፥ ከግብፅ ፡
ምድር ፡ ከወጡ ፡ በኋላ ፡ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡
፪፤ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፦— የእስራኤልን ፡
ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ድምር ፥ በየወገናቸው ፥
በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፥ በየስማቸው ፡ ቍጥር ፥
፫፤ ወንዱን ፡ በየራሱ ፥ ውሰዱ ። ከሀያ ፡ ዓመት ፡
ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያለውን ፥ ከእስራ
ኤል ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወጡትን ፡ ሁሉ ፥ አን
ተና ፡ አሮን ፡ በየሠራዊቶቻቸው ፡ ቍጠሩአቸው ።
፬፤ ከየነገዱም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ የአባቶቹ ፡ ቤት ፡
፭፤ አለቃ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይሁን ። ከእናንተም ፡
ጋር ፡ የሚቆሙት ፡ ሰዎች ፡ ስሞቻቸው ፡ እነ
ዚህ ፡ ናቸው ፤ ከሮቤል ፡ የሰዲዩር ፡ ልጅ ፡
፮፤ ኤሊሱር ፥ ከስምዖን ፡ የሱሪሰዳይ ፡ ልጅ ፡ ሰለ
፯፤ ሚኤል ፥ ከይሁዳ ፡ የአሚናዳብ ፡ ልጅ ፡ ነአ
፰፤ ሶን ፥ ከይሳኮር ፡ የሶገር ፡ ልጅ ፡ ናትናኤል ፥
፱፤፲፤ ከዛብሎን ፡ የኬሎን ፡ ልጅ ፡ ኤልያብ ፥ ከዮሴፍ ፡
ልጆች ፡ ከኤፍሬም ፡ የዓሚሁድ ፡ ልጅ ፡ ኤሊ
ሳማ ፥ ከምናሴ ፡ የፍዳሱር ፡ ልጅ ፡ ገማልኤል ፥
፲፩፤፲፪፤ ከብንያም ፡ የጋዴዮን ፡ ልጅ ፡ አቢዳን ፥ ከዳን ፡
፲፫፤ የአሚሳዳይ ፡ ልጅ ፡ አኪዔዘር ፥ ከአሴር ፡ የኤ
፲፬፤ ክራን ፡ ልጅ ፡ ፋግኤል ፥ ከጋድ ፡ የራጉኤል ፡
፲፭፤ ልጅ ፡ ኤሊሳፍ ፥ ከንፍታሌም ፡ የዔናን ፡ ልጅ ፡
፲፮፤ አኪሬ ። ከማኅበሩ ፡ የተመረጡ ፡ የእስራኤል ፡
አእላፍ ፡ ታላላቆች ፥ የአባቶቻቸው ፡ ነገድ ፡
፲፯፤ አለቆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። ሙሴና ፡ አሮንም ፡
እነዚህን ፡ በስማቸው ፡ የተጠሩትን ፡ ሰዎች ፡
፲፰፤ ወሰዱአቸው ፤ በሁለተኛውም ፡ ወር ፡ በመጀ
መሪያው ፡ ቀን ፡ ማኅበሩን ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰቡአ
ቸው ፤ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡
ያለውን ፡ በየራሱ ፡ በየወገኑም ፡ በየአባቶቻቸ
ውም ፡ ቤቶች ፡ በየስማቸው ፡ ቍጥር ፡ ትውል
፲፱፤ ዳቸውን ፡ ተናገሩ ። እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡
እንዳዘዘ ፡ እንዲሁ ፡ በሲና ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ቈጠ
ራቸው ።
፳፤ የእስራኤል ፡ በኵር ፡ የሮቤል ፡ ልጆች ፡ በየ
ትውልዳቸው ፥ በየወገናቸው ፥ በየአባቶቻ
ቸው ፡ ቤቶች ፥ እንደየስማቸው ፡ ቍጥር ፥ በየ
ራሳቸው ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡
በላይ ፡ ያለው ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡
፳፩፤ የሚወጡት ፡ ሁሉ ፥ ከሮቤል ፡ ነገድ ፡ የተቈ
ጠሩ ፡ አርባ ፡ ስድስት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡
ነበሩ ።
፳፪፤ የስምዖን ፡ ልጆች ፡ በየትውልዳቸው ፥ በየ
ወገናቸው ፥ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ የተቈ
ጠሩ ፥ እንደየስማቸው ፡ ቍጥር ፥ በየራሳቸው ፥
ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያለው ፡
ወንድ ፡ ሁሉ ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወጡት ፡ ሁሉ ፥
፳፫፤ ከስምዖን ፡ ነገድ ፡ የተቈጠሩት ፡ አምሳ ፡ ዘጠኝ ፡
ሺህ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።
፳፬፤ የጋድ ፡ ልጆች ፡ በየትውልዳቸው ፥ በየወገ
ናቸው ፥ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፥ እንደየስ
ማቸው ፡ ቍጥር ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚ
ያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወ
፳፭፤ ጡት ፡ ሁሉ ፥ ከጋድ ፡ ነገድ ፡ የተቈጠሩት ፡
አርባ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡
ነበሩ ።
፳፮፤ የይሁዳ ፡ ልጆች ፡ በየትውልዳቸው ፥ በየወ
ገናቸው ፥ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፥ እንደ
የስማቸው ፡ ቍጥር ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡

ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚ ወጡት ፡ ሁሉ ፥ ከይሁዳ ፡ ነገድ ፡ የተቈጠሩት ፡ ፳፯ ሰባ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፳፰ የይሳኮር ፡ ልጆች ፡ በየትውልዳቸው ፥ በየ ወገናቸው ፥ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፥ እንደ የስማቸው ፡ ቍጥር ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወ ጡት ፡ ሁሉ ፥ ከይሳኮር ፡ ነገድ ፡ የተቈጠሩት ፡ ፳፱ አምሳ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፴ የዛብሎን ፡ ልጆች ፡ በየትውልዳቸው ፥ በየወ ገናቸው ፥ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፥ እንደየስ ማቸው ፡ ቍጥር ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚ ያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወ ጡት ፡ ሁሉ ፥ ከዛብሎን ፡ ነገድ ፡ የተቈጠሩት ፡ ፴፩ አምሳ ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፴፪ ከዮሴፍ ፡ ልጆች ፥ የኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ በየት ውልዳቸው ፥ በየወገናቸው ፥ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፥ እንደየስማቸው ፡ ቍጥር ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወጡት ፡ ሁሉ ፥ ከኤፍሬም ፡ ነገድ ፡ ፴፫ የተቈጠሩት ፡ አርባ ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፴፬ የምናሴ ፡ ልጆች ፡ በየትውልዳቸው ፥ በየወ ገናቸው ፥ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፥ እንደየስ ማቸው ፡ ቍጥር ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚ ያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወጡት ፡ ሁሉ ፥ ከምናሴ ፡ ነገድ ፡ የተቈጠሩት ፡ ፴፭ ሠላሳ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፴፮ የብንያም ፡ ልጆች ፡ በየትውልዳቸው ፥ በየወ ገናቸው ፥ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፥ እንደየስ ማቸው ፡ ቍጥር ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚ ያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወጡት ፡ ሁሉ ፥ ከብንያም ፡ ነገድ ፡ የተቈጠሩት ፡ ፴፯ ሠላሳ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፴፰ የዳን ፡ ልጆች ፡ በየትውልዳቸው ፥ በየወገና ቸው ፥ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፥ እንደየስማ ቸው ፡ ቍጥር ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀመሮ ፡ ከዚ ያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወጡት ፡ ሁሉ ፥ ከዳን ፡ ነገድ ፡ የተቈጠሩት ፡ ፴፱ ስድሳ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፵ የአሴር ፡ ልጆች ፡ በየትውልዳቸው ፥ በየወገ ናቸው ፥ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፥ እንደየስ ማቸው ፡ ቍጥር ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚ ያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወጡት ፡ ሁሉ ፥ ከአሴር ፡ ነገድ ፡ የተቈጠሩት ፡ ፵፩ አርባ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፵፪ የንፍታሌም ፡ ልጆች ፡ በየትውልዳቸው ፥ በየ ወገናቸው ፥ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፥ እንደ የስማቸው ፡ ቍጥር ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚ ያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወጡት ፡ ሁሉ ፥ ከንፍታሌም ፡ ነገድ ፡ የተቈጠሩት ፡ ፵፫ አምሳ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፵፬ የተቈጠሩት ፥ ሙሴና ፡ አሮን ፡ አሥራ ፡ ሁለ ቱም ፡ የእስራኤል ፡ አለቆች ፡ የቈጠሩአቸው ፥ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ እያንዳንዱም ፡ የአባቶቹ ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ ነበረ ። ፵፭ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ የተቈጠሩት ፡ ሁሉ ፥ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፥ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወጡት ፡ ሁሉ ፥ የተቈጠሩት ፡ ፵፮ ሁሉ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ነበሩ ።

፵፯ ሌዋውያን ፡ ግን ፡ በየአባቶቻቸው ፡ ነገድ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ አልተቈጠሩም ። ፵፰ እግዚአብሔ ርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፦ ፵፱ የሌዊን ፡ ነገድ ፡ አትቍጠረው ፥ ቍጥራቸው ንም ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ አታድርግ ፤ ፶ ነገር ፡ ግን ፡ በምስክሩ ፡ ማደሪያና ፡ በዕቃዎች ፡ ሁሉ ፡ ለእርሱም ፡ በሚሆነው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሌዋውያንን ፡ አቁማቸው ። ማደሪያውንና ፡ ዕቃዎችን ፡ ሁሉ ፡ ይሸከሙ ፥ ያገለግሉትም ፥ በማደሪያውም ፡ ዙሪያ ፡ ይስፈሩ ። ፶፩ ማደሪያውም ፡ ሲነሣ ፡ ሌዋውያን ፡ ይንቀሉት ፤ ማደሪያውም ፡ በሰፈረ ፡ ጊዜ ፡ ሌዋውያን ፡ ይትከሉት ፤ ሌላ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ቢቀርብ ፡ ይገደል ። ፶፪ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እያንዳንዱ ፡ በየሰፈሩ ፥ በየዓላማውም ፥ በየጭፍራውም ፡ ይሰፍራሉ ። ፶፫ ነገር ፡ ግን ፡ በእ ስራኤል ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ቍጣ ፡ እንዳይወርድ ፡ ሌዋውያን ፡ በምስክሩ ፡ ማደሪያ ፡ ዙሪያ ፡ ይስ ፈሩ ፤ ሌዋውያንም ፡ የምስክሩን ፡ ማደሪያ ፡ ይጠ ብቁ ። ፶፬ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ፤ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ፡ እን ዲሁ ፡ አረደጉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ለሙሴና ፡ ለአሮን ፡ እን ዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ፦ ፪ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እያንዳንዱ ፡ በየዓላማው ፡ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ ምልክት ፡ ይስፈሩ ፤ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ አፋዛዥ ፡ ዙሪያ ፡ ይስፈሩ ። ፫ በምሥ ራቅ ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ፀሐይ ፡ መውጫ ፡ የሚሰ ፍሩት ፡ እንደ ፡ ሠራዊቶቻቸው ፡ የይሁዳ ፡ ሰፈር ፡ ዓላማ ፡ ሰዎች ፡ ይሆናሉ ፤ የይሁዳ ፡ ልጆችም ፡ አለቃ ፡ የአሚናዳብ ፡ ልጅ ፡ ነአሶን ፡ ነበረ ። ፬ ሠራዊቱም ፥ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩ ፡ ሰባ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። ፭ በእነር ሱም ፡ አጠገብ ፡ የሚሰፍሩ ፡ የይሳኮር ፡ ነገድ ፡ ይሆናሉ ፤ የይሳኮርም ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የሶ ገር ፡ ልጅ ፡ ናትናኤል ፡ ነበረ ። ፮ ሠራዊቱም ፥ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩ ፡ አምሳ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። ፯ በእነርሱም ፡ አጠገብ ፡ የዛብሎን ፡ ነገድ ፡ ነበረ ፤ የዛብሎንም ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የኬሎን ፡ ልጅ ፡ ኤልያብ ፡ ነበረ ። ፰ ሠራ ዊቱም ፥ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩ ፡ አምሳ ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። ፱ ከይሁዳ ፡ ሰፈር ፡ የተቈጠሩ ፡ ሁሉ ፡ በየሠራዊቶቻቸው ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ ስድስት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። እነዚህም ፡ አስቀድመው ፡ ይጓዛሉ ።

፲ በደቡብ ፡ በኩል ፡ በየሠራዊቶቻቸው ፡ የሮ

ቤል ፡ ሰፈር ፡ ዓላማ ፡ ይሆናል ፤ የሮቤልም ፡
ልጆች ፡ አለቃ ፡ የሰዲዮር ፡ ልጅ ፡ ኤሊሱር ፡
፲፩ ነበረ ። ሠራዊቱም ÷ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩ ፡
አርባ ፡ ስድስት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።
፲፪ በእነርሱም ፡ አጠገብ ፡ የሚሰፍሩ ፡ የስምዖን ፡
ነገድ ፡ ናቸው ፤ የስምዖንም ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡
፲፫ የሱሪሰዳይ ፡ ልጅ ፡ ሰለሚኤል ፡ ነበረ ። ሠራ
ዊቱም ÷ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩ ፡ አምሳ ፡
፲፬ ዘጠኝ ፡ ሺህ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። በእነር
ሱም ፡ አጠገብ ፡ የጋድ ፡ ነገድ ፡ ነበረ ፤ የጋድም ፡
ልጆች ፡ አለቃ ፡ የራጉኤል ፡ ልጅ ፡ ኤሊሳፍ ፡
፲፭ ነበረ ። ሠራዊቱም ÷ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩ ፡
አርባ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡
፲፮ ነበሩ ። ከሮቤል ፡ ሰፈር ፡ የተቈጠሩ ፡ ሁሉ ፡
በየሠራዊቶቻቸው ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡
አራት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ነበሩ ። እነርሱም ፡ ቀጥ
ለው ፡ ይጓዛሉ ።

፲፯ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ በሰ
ፈሮቹም ፡ መካከል ፡ የሌዋውያን ፡ ሰፈር ፡ ይጓ
ዛል ፤ እንደ ፡ ሰፈራቸው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በየስ
ፍራው ፡ በየዓላማውም ፡ ይጓዛሉ ።

፲፰ በምዕራብ ፡ በኩል ፡ እንደ ፡ ሠራዊቶቻቸው ፡
የኤፍሬም ፡ ሰፈር ፡ ዓላማ ፡ ይሆናል ፤ የኤፍ
ሬም ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የዓሚሁድ ፡ ልጅ ፡ ኤሊ
፲፱ ሳማ ፡ ነበረ ። ሠራዊቱም ÷ ከእነርሱም ፡ የተ
ቈጠሩ ፡ አርባ ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።
፳ በእነርሱም ፡ አጠገብ ፡ የምናሴ ፡ ነገድ ፡ ይሆ
ናል ፤ የምናሴም ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የፍዳሱር ፡
፳፩ ልጅ ፡ ገማልኤል ፡ ነበረ ። ሠራዊቱም ÷ ከእ
ነርሱም ፡ የተቈጠሩ ፡ ሠላሳ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡
፳፪ ሁለት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። በእነርሱም ፡ አጠገብ ፡
የብንያም ፡ ነገድ ፡ ይሆናል ፤ የብንያምም ፡
ልጆች ፡ አለቃ ፡ የጋዴዮን ፡ ልጅ ፡ አቢዳን ፡
፳፫ ነበረ ። ሠራዊቱም ÷ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩ ፡
ሠላሳ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።
፳፬ ከኤፍሬም ፡ ሰፈር ፡ የተቈጠሩ ፡ ሁሉ ፡ በየሠራ
ዊቶቻቸው ፡ መቶ ፡ ስምንት ፡ ሺህ ፡ አንድ ፡
መቶ ፡ ነበሩ ። እነርሱም ፡ ሦስተኛ ፡ ሆነው ፡
ይጓዛሉ ።

፳፭ በሰሜን ፡ በኩል ፡ እንደ ፡ ሠራዊቶቻቸው ፡
የዳን ፡ ሰፈር ፡ ዓላማ ፡ ይሆናል ፤ የዳንም ፡
ልጆች ፡ አለቃ ፡ የአሚሳዳይ ፡ ልጅ ፡ አኪዔዘር ፡
፳፮ ነበረ ። ሠራዊቱም ÷ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩ ፡
ስድሳ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።
፳፯ በእነርሱም ፡ አጠገብ ፡ የሚሰፍሩ ፡ የአሴር ፡
ነገድ ፡ ይሆናሉ ፤ የአሴርም ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡
፳፰ የኤክራን ፡ ልጅ ፡ ፋግኤል ፡ ነበረ ። ሠራዊ
ቱም ÷ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩ ፡ አርባ ፡ አንድ ፡
፳፱ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። በእነርሱም ፡
አጠገብ ፡ የንፍታሌም ፡ ነገድ ፡ ይሆናል ፤ የን
ፍታሌምም ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የዔናን ፡ ልጅ ፡
፴ አኪሬ ፡ ነበረ ። ሠራዊቱም ÷ ከእነርሱም ፡ የተ
ቈጠሩ ፡ አምሳ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡
፴፩ ነበሩ ። ከዳን ፡ ሰፈር ፡ የተቈጠሩ ፡ ሁሉ ፡ መቶ ፡
አምሳ ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።
እነርሱም ፡ በየዓላሞቻቸው ፡ በመጨረሻ ፡ ይጓ
ዛሉ ።

፴፪ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በየአባቶቻቸው ፡
ቤቶች ፡ የተቈጠሩ ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ከየሰ
ፈሩ ፡ በየሠራዊቶቻቸው ፡ የተቈጠሩ ፡ ሁሉ ፡
ስድስት ፡ መቶ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡
፴፫ አምሳ ፡ ነበሩ ። ሌዋውያን ፡ ግን ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘ ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡
፴፬ ጋር ፡ አልተቈጠሩም ። የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
እንዲሁ ፡ አደረጉ ፤ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡
እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ በዓላሞቻቸው ፡
አጠገብ ፡ ሰፈሩ ÷ እንዲሁም ፡ በየወገኖቻቸው ፡
በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ ተጓዙ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ በሲና ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡
ሙሴን ፡ በተናገረበት ፡ ቀን ፡ የአሮንና ፡ የሙሴ ፡
፪ ትውልድ ፡ ይህ ፡ ነበረ ። የአሮን ፡ ልጆች ፡ ስም ፡
ይህ ፡ ነው ፤ በኵሩ ፡ ናዳብ ÷ አብዩድ ÷ አልዓ
፫ ዛር ÷ ኢታምር ። የተቀቡ ፡ ካህናት ፡ በክህነ
ትም ፡ ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡ የቀደሳቸው ፡ የአሮን ፡
፬ ልጆች ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ። ናዳብና ፡ አብዩድ ፡
በሲና ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ልዩ ፡ እሳት ፡ በቀረቡ ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ሞቱ ፤ ልጆችም ፡ አልነበሩአቸውም ።
አልዓዛርና ፡ ኢታምር ፡ በአባታቸው ፡ በአሮን ፡
ፊት ፡ በክህነት ፡ ያገለግሉ ፡ ነበር ።

፭ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፮ ተናገረው ፦— የሌዊን ፡ ነገድ ፡ አቅርበህ ፡ ያገለ
ግሉት ፡ ዘንድ ፡ በካህኑ ፡ በአሮን ፡ ፊት ፡ አቁማ
፯ ቸው ። የማደሪያውንም ፡ ሥራ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ÷
እርሱንና ፡ ማኅበሩን ፡ ሁሉ ፡ ለማገልገል ፡ የሚ
ያስፈልገውን ፡ ነገር ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡
፰ ፊት ፡ ይጠብቁ ። የማደሪያውንም ፡ ሥራ ፡
ይሠሩ ፡ ዘንድ ÷ የመገናኛውን ፡ ድንኳን ፡ ዕቃ ፡
ሁሉ ፡ ይጠብቁ ÷ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ለማ
ገልገል ፡ የሚያስፈልገውንም ፡ ነገር ፡ ይጠብቁ ።
፱ ሌዋውያንንም ፡ ለአሮንና ፡ ለልጆቹ ፡ ትሰጣለህ ፤
ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ለእርሱ ፡ ፈጽመው ፡
፲ ተሰጡ ። አሮንንና ፡ ልጆቹን ፡ አቁማቸው ÷
ክህነታቸውንም ፡ ይጠብቁ ፤ ሌላ ፡ ሰውም ፡
ቢቀርብ ፡ ይገደል ።

፲፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፲፪ ተናገረው ፦— እነሆ ÷ እኔ ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ዘንድ ፡ ማኅፀን ፡ በሚከፍተው ፡ በበኵሩ ፡ ሁሉ ፡
ፋንታ ፡ ሌዋውያንን ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡
፲፫ መካከል ፡ ወስጃለሁ ፤ በኵር ፡ ሁሉ ፡ ለእኔ ፡
ነውና ፡ ሌዋውያን ፡ ለእኔ ፡ ይሁኑ ፤ በግብፅ ፡
ምድር ፡ በኵርን ፡ ሁሉ ፡ በመታሁ ፡ ቀን ÷ ከእ
ስራኤል ፡ ዘንድ ፡ በኵርን ፡ ሁሉ ÷ ሰውንና ፡
እንስሳን ÷ ለእኔ ፡ ለይቼአለሁ ፤ ለእኔ ፡ ይሁኑ ።
እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ።

፲፬ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ በሲና ፡ ምድረ ፡

፲፭ ፡ በዳ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— የሌዊን ፡ ልጆች ፡ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ በየወገናቸ ውም ፡ ቍጠር ፤ ወንዱን ፡ ሁሉ ፡ ከአንድ ፡ ወር ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያለውን ፡ ቍጠራቸው ።
፲፮ ፡ ሙሴም ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንዳዘ
፲፯ ፡ ዘው ፡ ቈጠራቸው ። የሌዊ ፡ ልጆች ፡ በየስማ ቸው ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ጌድሶን ፥ ቀዓት ፥
፲፰ ፡ ሜራሪ ። የጌድሶንም ፡ ልጆች ፡ ስሞች ፡ በየወ ገናቸው ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ሎቤኒ ፥ ሰሜኢ ።
፲፱ ፡ የቀዓትም ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፤ እንበረም ፥
፳ ፡ ይስዓር ፥ ኬብሮን ፥ ዑዝኤል ። የሜራሪም ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፤ ሞሖሊ ፥ ሙሲ ። የሌዋ ውያን ፡ ወገኖች ፡ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ እነ ዚህ ፡ ናቸው ።

፳፩ ፡ ለጌድሶን ፡ የሎቤናውያን ፡ ወገን ፡ የሰሜአው ያንም ፡ ወገን ፡ ነበሩት ፤ የጌድሶናውያን ፡ ወገ
፳፪ ፡ ኖች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። ከእነርሱ ፡ የተቈጠሩት ፡ የወንዶች ፡ ሁሉ ፡ ቍጥር ፡ ከአንድ ፡ ወር ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ የተቈጠሩት ፡ ሰባት ፡
፳፫ ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። የጌድሶናውያን ፡ ወገኖች ፡ ከማደሪያው ፡ በኋላ ፡ በምዕራብ ፡
፳፬ ፡ በኩል ፡ ይሰፍራሉ ። የጌድሶናውያንም ፡ አባ ቶች ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ የዳኤል ፡ ልጅ ፡ ኤሊሳፍ ፡
፳፭ ፡ ይሆናል ። ጌድሶናውያንም ፡ በመገናኛው ፡ ድን ኳን ፡ የሚጠብቁት ፡ ማደሪያው ፥ ድንኳኑም ፥ መደረቢያውም ፥ የመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡
፳፮ ፡ መጋረጃ ፥ በማደሪያውና ፡ በመሠዊያው ፡ ዙሪያ ፡ ያለው ፡ የአደባባዩ ፡ መጋረጆች ፥ የአደባባዩም ፡ ደጃፍ ፡ መጋረጃ ፥ ለማገልገሉም ፡ ያሉት ፡ ገመ ዶች ፡ ሁሉ ፡ ይሆናል ።

፳፯ ፡ ከቀዓትም ፡ የእንበረማውያን ፡ ወገን ፥ የይስዓ ራውያንም ፡ ወገን ፥ የኬብሮናውያንም ፡ ወገን ፥ የዑዝኤላውያንም ፡ ወገን ፡ ነበሩ ፤ የቀዓታው
፳፰ ፡ ያን ፡ ወገኖች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። ወንዶች ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ቍጥራቸው ፡ ከአንድ ፡ ወር ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ስምንት ፡ ሺህ ፡ ስድ ስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ፤ መቅደሱንም ፡ ይጠብቁ ፡
፳፱ ፡ ነበር ። የቀዓት ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ በማደሪያው ፡
፴ ፡ አጠገብ ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ይሰፍራሉ ። የቀዓ ታውያንም ፡ ወገኖች ፡ አባቶች ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡
፴፩ ፡ የዑዝኤል ፡ ልጅ ፡ ኤሊሳፈን ፡ ይሆናል ። ታቦ ቱንም ፥ ገበታውንም ፥ መቅረዙንም ፥ መሠዊያ ዎቹንም ፥ የሚያገለግሉበትንም ፡ የመቅደሱን ፡ ዕቃ ፥ መጋረጃውንም ፥ ማገልገያውንም ፡ ሁሉ ፡
፴፪ ፡ ይጠብቃሉ ። የሌዋውያንም ፡ አለቆች ፡ አለቃ ፡ የካህኑ ፡ የአሮን ፡ ልጅ ፡ አልዓዛር ፡ ይሆናል ፤ እርሱም ፡ መቅደሱን ፡ በሚጠብቁት ፡ ላይ ፡ ይሆ ናል ።

፴፫ ፡ ከሜራሪ ፡ የሞሖላያውያን ፡ ወገን ፡ የሙሳያው ያንም ፡ ወገን ፡ ነበሩ ፤ የሜራሪ ፡ ወገኖች ፡ እነዚህ ፡
፴፬ ፡ ናቸው ። ከእነርሱም ፡ ወንዶች ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ቍጥራቸው ፡ ከአንድ ፡ ወር ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ የተቈጠሩት ፡ ስድስት ፡ ሺህ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።
፴፭ ፡ የሜራሪም ፡ ወገኖች ፡ አባቶች ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ የአቢካኢል ፡ ልጅ ፡ ሱሪኤል ፡ ነበረ ፤ በማደሪያው ፡ አጠገብ ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡
፴፮ ፡ ይሰፍራሉ ። የሜራሪም ፡ ልጆች ፡ የሚጠብቁት ፡ የማደሪያው ፡ ሳንቆች ፥ መወርወሪያዎችም ፥ ተራዳዎችም ፥ እግሮቹም ፥ ዕቃውም ፡ ሁሉ ፥
፴፯ ፡ ማገልገያውም ፡ ሁሉ ፥ በዙሪያውም ፡ የሚቆሙ ፡ የአደባባይ ፡ ምሰሶች ፥ እግሮቹም ፥ ካስማዎቹም ፥ አውታሮቹም ፡ ይሆናሉ ።

፴፰ ፡ በማደሪያውም ፡ ፊት ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ፊት ፡ በስተ ፡ ፀሐይ ፡ መውጫ ፡ የሚሰፍሩት ፡ ሙሴና ፡ አሮን ፡ ልጆ ቹም ፡ ይሆናሉ ፥ መቅደሱንም ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ይጠብቃሉ ፤ ልዩም ፡ ሰው ፡ ቢቀርብ ፡ ይገደል ።

፴፱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ ሙሴና ፡ አሮን ፡ የቈጠሩአቸው ፥ ከሌዋውያን ፡ ወንዶች ፡ ሁሉ ፡ ከአንድ ፡ ወር ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ በየወ ገናቸው ፡ የተቈጠሩት ፡ ሁሉ ፡ ሀያ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ነበሩ ።

፵ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ወንዱን ፡ በኵር ፡ ሁሉ ፡ ቍጠር ፤ ከአ ንድ ፡ ወር ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያሉትን ፡
፵፩ ፡ የስማቸውን ፡ ቍጥር ፡ ውሰድ ፤ ሌዋውያንንም ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በኵር ፡ ሁሉ ፡ ፋንታ ፥ የሌዋውያንንም ፡ እንስሶች ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንስሶች ፡ በኵር ፡ ሁሉ ፡ ፋንታ ፡ ለእኔ ፡
፵፪ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ውሰድ ፡ አለው ። ሙሴም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ የእስራኤልን ፡
፵፫ ፡ ልጆች ፡ በኵር ፡ ሁሉ ፡ ቈጠረ ። ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩ ፡ ወንዶች ፡ በኵሮች ፡ ሁሉ ፡ በየስማ ቸው ፡ ከአንድ ፡ ወር ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ሀያ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡ ሦስት ፡ ነበሩ ።

፵፬ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፵፭ ፡ ተናገረው ፡— ሌዋውያንን ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በኵር ፡ ሁሉ ፡ ፋንታ ፥ የሌዋውያንንም ፡ እንስ ሶች ፡ በእንስሶቻቸው ፡ ፋንታ ፡ ውሰድ ፤ ሌዋው ያንም ፡ ለእኔ ፡ ይሁኑ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ።
፵፮ ፡ በሌዋውያን ፡ ላይ ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በኵር ፡ ስለ ፡ ተረፉት ፡ ስለ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡ ሦስት ፡
፵፯ ፡ ቤዛ ፥ በየራሱ ፡ አምስት ፡ ሰቅል ፡ ውሰድ ፤ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ ትወስዳለህ ፤ ሰቅ
፵፰ ፡ ሉም ፡ ሀያ ፡ አቦሊ ፡ ነው ። ስለ ፡ ተረፉትም ፡ የመቤዣውን ፡ ገንዘብ ፡ ለአሮንና ፡ ለልጆቹ ፡
፵፱ ፡ ስጥ ። ሙሴም ፡ በሌዋውያን ፡ ከተቤዡት ፡ በላይ ፡ ከተረፉት ፡ ዘንድ ፡ የመቤዣውን ፡ ገን
፶ ፡ ዘብ ፡ ወሰደ ። ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በኵሮች ፡ ገንዘቡን ፡ ሺህ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ አም ስት ፡ ሰቅል ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡
፶፩ ፡ ወሰደ ። እንደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ቃል ፥ እግዚ አብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፥ ሙሴ ፡ የመቤ ዣውን ፡ ገንዘብ ፡ ለአሮንና ፡ ለልጆቹ ፡ ሰጠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ እግዚአብሔርም፡ሙሴንና፡አሮንን፡እንዲህ፡
፪ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— ከሌዊ ፡ ልጆች ፡ መካ
ከል ፡ በየወገናቸው ፡ በየአባቶቻቸው፡ቤቶች፡
፫ የቀዓትን ፡ ልጆች ፡ ድምር ፡ ውሰድ ፤ ከሠላሳ ፡
ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አምሳ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡
በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ለአገ
ልግሎት ፡ የሚገቡበትን ፡ ሁሉ ፡ ትደምራለህ ።
፬ በመገናኛው፡ድንኳን፡በንዋየ፡ቅድሳቱ፡ዘንድ፡
፭ የቀዓት ፡ ልጆች ፡ ሥራ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ከሰፈሩ ፡
በተነሡ ፡ ጊዜ ፡ አሮንና ፡ ልጆቹ ፡ ገብተው ፡ የሚ
ሸፍነውን ፡ መጋረጃ ፡ ያውርዱ ፥ የምስክሩንም ፡
፮ ታቦት ፡ ይጠቅልሉበት ፤ በላዩም ፡ የአቆስጣ
ውን ፡ ቁርበት ፡ መሸፈኛ ፡ ያድርጉበት ፥ ከእር
ሱም ፡ በላይ ፡ ሁለንተናው ፡ ሰማያዊ ፡ የሆነ ፡
መጐናጸፊያ ፡ ይዘርጉበት ፥ መሎጊያዎቹንም ፡
፯ ያግቡ ። በገጽ ፡ ኅብስት ፡ ገበታ ፡ ላይ ፡ ሰማያ
ዊውን ፡ መጐናጸፊያ ፡ ይዘርጉበት ፤ በእርሱም ፡
ላይ ፡ ወጭቶቹን ፥ ጭልፋዎቹንም ፥ ጽዋዎቹ
ንም ፥ ለማፍሰስም ፡ መቅጃዎቹን ፡ ያድርጉ ፤
ሁልጊዜም ፡ የሚኖር ፡ እንጀራ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡
፰ ይሁን ። በእነርሱም ፡ ላይ ፡ ቀይ ፡ መጐናጸፊያ ፡
ይዘርጉ ፥ በአቆስጣውም ፡ ቁርበት ፡ መሸፈኛ ፡
፱ ይሸፍኑት ፥ መሎጊያዎቹንም ፡ ያግቡ ። ሰማያ
ዊውንም ፡ መጐናጸፊያ ፡ ይውሰዱ ፥ የሚያበ
ራውንም ፡ መቅረዝ ፥ ቀንዲሎቹንም ፥ መኰስ
ተሪያዎቹንም ፥ የኩስታሪ፡ማድረጊያዎቹንም ፥
እርሱንም ፡ ለማገልገል ፡ የዘይቱን ፡ ዕቃዎች ፡
፲ ሁሉ ፡ ይሸፍኑ ፤ እርሱንና ፡ ዕቃዎቹን ፡ ሁሉ ፡
በአቆስጣ ፡ ቁርበት ፡ መሸፈኛ ፡ ውስጥ ፡ ያድ
ርጉ ፥ በመሸከሚያውም ፡ ላይ ፡ ያድርጉት ።
፲፩ በወርቁም ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ ሰማያዊውን ፡ መጐ
ናጸፊያ ፡ ይዘርጉበት ፥ በአቆስጣም ፡ ቁርበት ፡
መሸፈኛ ፡ ይሸፍኑት ፥ መሎጊያዎቹንም ፡ ያግቡ ።
፲፪ በመቅደስም ፡ ውስጥ ፡ የሚያገለግሉበትን ፡
የማገልገያውን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ይውሰዱ ፥ በሰ
ማያዊውም ፡ መጐናጸፊያ ፡ ውስጥ ፡ ያስቀም
ጡት ፥ በአቆስጣም ፡ ቁርበት ፡ መሸፈኛ ፡ ይሸ
ፍኑት ፥ በመሸከሚያውም ፡ ላይ ፡ ያድርጉት ።
፲፫ አመዱንም ፡ ከመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያስወግዱ ፥
ሐምራዊውንም ፡ መጐናጸፊያ ፡ ይዘርጉበት ፤
፲፬ የሚያገለግሉበትን ፡ ዕቃውን ፡ ሁሉ ፥ ማንደጃ
ዎቹን ፡ ሜንጦቹንም ፡ መጫሪያዎቹንም ፡ ድስ
ቶቹንም ፥ የመሠዊያውን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ያስቀ
ምጡበት ፤ በእርሱም ፡ የአቆስጣን ፡ ቁርበት ፡
መሸፈኛ ፡ ይዘርጉ ፥ መሎጊያዎቹንም ፡ ያግቡ ።
፲፭ ከሰፈሩም ፡ ሲነሡ ፥ አሮንና ፡ ልጆቹ ፡ መቅደ
ሱንና ፡ የመቅደሱን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ከሸፈኑ ፡
በኋላ ፥ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የቀዓት ፡ ልጆች ፡ ሊሸ
ከሙት ፡ ይመጣሉ ፤ እንዳይሞቱ ፡ ግን ፡ ንዋየ ፡
ቅድሳቱን ፡ አይንኩ ። በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡
ዘንድ ፡ የቀዓት ፡ ልጆች ፡ ሸክም ፡ ይህ ፡ ነው ።
፲፮ የካህኑም ፡ የአሮን ፡ ልጅ ፡ አልዓዛር ፡ በመ
ብራቱ ፡ ዘይት ፡ በጣፋጩም ፡ ዕጣን ፡ ላይ ፥
ሁልጊዜም ፡ በሚቀርበው ፡ በእህሉ ፡ ቍርባ
ንና ፡ በቅባቱ ፡ ዘይት ፡ ላይ ፡ ይሾም ፤ ማደሪያ
ውን ፡ ሁሉ ፥ በእርሱም ፡ ውስጥ ፡ ያለውን ፡
ሁሉ ፥ መቅደሱንና ፡ ዕቃውን ፡ ይጠብቃል ።
፲፯ እግዚአብሔር ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ እንዲህ ፡
፲፰ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— የቀዓትን ፡ ወገኖች ፡ ነገድ ፡
፲፱ ከሌዋውያን ፡ መካከል ፡ አታጥፉአቸው ፤ ነገር ፡
ግን ፡ ወደ ፡ ቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፡ በቀረቡ ፡ ጊዜ ፡
በሕይወት ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡ እንጂ ፡ እንዳይሞቱ ፡
እንዲሁ ፡ አድርጉላቸው ፤ አሮንና ፡ ልጆቹ ፡
ይግቡ ፥ ለሰውም ፡ ሁሉ ፡ ሥራውንና ፡ ሸክሙን ፡
፳ ይዘዙ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እንዳይሞቱ ፡ ንዋየ ፡ ቅድ
ሳቱን ፡ ለድንገት ፡ እንኳ ፡ ለማየት ፡ አይግቡ ።
፳፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፳፪ ተናገረው ፡— የጌድሶንን ፡ ልጆች ፡ ድምር ፡
ደግሞ ፡ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ በየወገኖቻ
ቸውም ፡ ውሰድ ። የመገናኛውን ፡ ድንኳን ፡
፳፫ ሥራ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ለአገልግሎት ፡ የሚገቡ
ትን ፡ ሁሉ ፡ ከሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
አምሳ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ቍጠራቸው ። የጌድ
፳፬ ሶናውያን ፡ ወገኖች ፡ ሥራ ፡ በማገልገልና ፡ በመ
ሸከም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የማደሪያውን ፡ መጋረጆች ፥
፳፭ የመገናኛውንም ፡ ድንኳን ፥ መደረቢያውን ፥
በላዩም ፡ ያለውን ፡ የአቆስጣውን ፡ ቁርበት ፡
መደረቢያ ፥ የመገናኛውንም ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡
መጋረጃ ፥ በማደሪያውና ፡ በመሠዊያው ፡ ዙሪያ ፡
፳፮ ያለውን ፡ የአደባባዩን ፡ መጋረጃ ፥ የአደባባዩ
ንም ፡ ደጃፍ ፡ መጋረጃ ፥ አውታሮቻቸውንም ፥
ለማገልገልም ፡ የሚሠሩበትን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ይሸ
ከሙ ፤ በዚህ ፡ ያገልግሉ ። የጌድሶናውያን ፡ አገ
፳፯ ልግሎት ፡ ሁሉ ፥ ሸክማቸውም ፡ ሁሉ ፥ ሥራ
ቸውም ፡ ሁሉ ፡ በአሮንና ፡ በልጆቹ ፡ ትእዛዝ ፡
ይሁን ፤ የሚደርስባቸውንም ፡ ሸክም ፡ ሁሉ ፡ ትነ
ግሩአቸዋላችሁ ። የጌድሶናውያን ፡ ወገኖች ፡
፳፰ አገልግሎት ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ዘንድ ፡
ይህ ፡ ነው ፤ ከካህኑ ፡ ከአሮን ፡ ልጅ ፡ ከኢታምር ፡
እጅ ፡ በታች ፡ ይሆናሉ ።
፳፱ የሜራሪንም ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፡ በየአ
፴ ባቶቻቸውም ፡ ቤቶች ፡ ቍጠራቸው ። የመገ
ናኛውን ፡ ድንኳን ፡ ሥራ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ለአ
ገልግሎት ፡ የሚገቡትን ፡ ሁሉ ፡ ከሠላሳ ፡ ዓመት ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አምሳ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ቍጠ
፴፩ ራቸው ። በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ዘንድ ፡ በለው ፡
አገልግሎታቸው ፡ ሁሉ ፥ የማደሪያው ፡ ሳን
ቆች ፥ መወርወሪያዎቹም ፥ ተራዳዎቹም ፥ እግ
፴፪ ሮቹም ፥ በዙሪያውም ፡ የሚቆሙት ፡ የአደባ
ባዩ ፡ ምሰሶች ፥ እግሮቹም ፥ ካስማዎቹም ፥ አው
ታሮቹም ፥ ዕቃዎቹና ፡ ማገልገያዎቹ ፡ ሸክማ
ቸው ፡ ነው ፤ የሚጠብቁትንም ፡ የሸክማቸውን ፡
፴፫ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ በስማቸው ፡ ቍጠሩ ። የሜራሪ ፡
ልጆች ፡ ወገኖች ፡ አገልግሎት ፡ በመገናኛው ፡
ድንኳን ፡ ዘንድ ፡ ከካህኑ ፡ ከአሮን ፡ ልጅ ፡ ከኢ
ታምር ፡ እጅ ፡ በታች ፡ በየአገልግሎታቸው ፡

ሁሉ ፡ ይህ ፡ ነው ።

፴፬ ሙሴና ፡ አሮንም ፡ የሕዝቡም ፡ አለቆች ፡ የቀዓትን ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፡ በየአባቶቻቸውም ፡ ቤቶች ፡ ቈጠሩአቸው ። ፴፭ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ አገልግሎት ፡ የገቡትን ፡ ሁሉ ፡ ከሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አምሳ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ያሉትን ፡ ፴፮ ቈጠሩአቸው ፤ በየወገናቸውም ፡ ከእነርሱ ፡ የተቈጠሩት ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ፴፯ አምሳ ፡ ነበሩ ። እግዚአብሔር ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ እንዳዘዘ ፥ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ያገለገሉት ፡ ሁሉ ፥ ከቀዓታውያን ፡ ወገኖች ፡ የተቈጠሩት ፥ ሙሴና ፡ አሮን ፡ የቈጠሩአቸው ፥ እነዚህ ፡ ናቸው ።

፴፰ በየወገናቸውም ፡ በየአባቶቻቸውም ፡ ቤቶች ፡ ፴፱ የተቈጠሩት ፡ የጌድሶን ፡ ልጆች ፥ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ለአገልግሎት ፡ የገቡት ፥ ከሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ፵ አምሳ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ያሉት ፥ በየወገናቸውም ፡ በየአባቶቻቸውም ፡ ቤቶች ፡ የተቈጠሩት ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ፵፩ ነበሩ ። እግዚአብሔር ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ እንዳዘዘ ፥ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ያገለገሉት ፡ ሁሉ ፥ ከጌድሶን ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ የተቈጠሩት ፥ ሙሴና ፡ አሮን ፡ የቈጠሩአቸው ፥ እነዚህ ፡ ናቸው ።

፵፪ በየወገናቸውም ፡ በየአባቶቻቸውም ፡ ቤቶች ፡ ከሜራሪ ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ የተቈጠሩት ፥ ፵፫ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ወደ ፡ አገልግሎት ፡ የገቡት ፡ ሁሉ ፡ ከሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አምሳ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ያሉት ፥ ፵፬ በየወገናቸው ፡ የተቈጠሩት ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ፵፭ ሁለት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። እግዚአብሔር ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ እንዳዘዘ ፥ ከሜራሪ ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ የተቈጠሩት ፥ ሙሴና ፡ አሮን ፡ የቈጠሩአቸው ፥ እነዚህ ፡ ናቸው ።

፵፮ በየወገናቸውና ፡ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ ከሌዋውያን ፡ የተቈጠሩት ፡ ሁሉ ፥ ሙሴና ፡ አሮን ፡ የእስራኤልም ፡ አለቆች ፡ የቈጠሩአቸው ፥ ፵፯ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ሥራውን ፡ ለመሥራትና ፡ ዕቃውን ፡ ለመሸከም ፡ የገቡት ፡ ሁሉ ፥ ከሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አምሳ ፡ ፵፰ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ያሉት ፥ ከእነርሱ ፡ የተቈጠሩት ፡ ስምንት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ ፵፱ ነበሩ ። እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ እያንዳንዳቸው ፡ በየአገልግሎታቸውና ፡ በየሸክማቸው ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ ተቈጠሩ ፤ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘ ፡ እንዲሁ ፡ በእርሱ ፡ ተቈጠሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፪ ተናገረው ፦— የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ለምጻሙን ፡ ሁሉ ፥ ፈሳሽ ፡ ነገርም ፡ ያለበትን ፡ ሁሉ ፥ በሬሳም ፡ የረከሰውን ፡ ሁሉ ፡ ከሰፈሩ ፡ እንዲያወጡ ፡ እዘዛቸው ፤ ፫ ወንዱንና ፡ ሴቱን ፡ አውጡ ፤ እኔ ፡ በመካከሉ ፡ የማድርበትን ፡ ሰፈራቸውን ፡ እንዳያረክሱ ፡ ከሰፈሩ ፡ አውጡአቸው ። ፬ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ፥ ከሰፈሩ ፡ አወጡአቸው ፤ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፥ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ።

፭ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፮ ተናገረው ፦— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ንገራቸው ፦— ወንድ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ይተላለፍ ፡ ዘንድ ፡ ሰው ፡ የሚሠራውን ፡ ኃጢአት ፡ ቢሠራ ፥ በዚያም ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ በደል ፡ ቢሆን ፥ በሠራው ፡ ኃጢአት ፡ ይናዘዝ ፤ ፯ የወሰደውንም ፡ በሙሉ ፡ ይመልስ ፡ አምስተኛውንም ፡ ይጨምርበት ፥ ለበደለውም ፡ ሰው ፡ ይስጠው ። ፰ ነገር ፡ ግን ፡ ይመልስለት ፡ ዘንድ ፡ ሰውዮው ፡ ዘመድ ፡ ባይኖረው ፥ ስለ ፡ በደል ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚመልሰው ፡ ነገር ፡ ለካህኑ ፡ ይሁን ፥ ይህም ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ማስተስረያ ፡ ከሚደረግበት ፡ አውራ ፡ በግ ፡ በላይ ፡ ይጨመር ። ፱ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ለካህኑ ፡ የሚያቀርቡት ፡ የተቀደሰ ፡ የማንሣት ፡ ቍርባን ፡ ሁሉ ፡ ለእርሱ ፡ ፲ ይሁን ። የተቀደሰ ፡ የሰው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፥ ሰውም ፡ ለካህኑ ፡ የሚሰጠው ፡ ሁሉ ፡ ለእርሱ ፡ ይሁን ።

፲፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፲፪ ተናገረው ፦— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ንገራቸው ፦— የማንኛውም ፡ ሰው ፡ ሚስት ፡ ከእርሱ ፡ ፈቀቅ ፡ ፲፫ ብትል ፥ በእርሱም ፡ ላይ ፡ ብትበድል ፥ ከሌላም ፡ ሰው ፡ ጋር ፡ ብትተኛ ፥ ከባልዋም ፡ ዓይን ፡ ቢሸሽግ ፥ እርስዋም ፡ ተሰውራ ፡ ብትረክስ ፥ ምስክርም ፡ ባይኖርባት ፥ በምንዝርም ፡ ባትገኝ ፥ ፲፬ በባልዋም ፡ ላይ ፡ የቅንዓት ፡ መንፈስ ፡ ቢመጣበት ፥ እርስዋም ፡ ስትረክስ ፡ ስለ ፡ ሚስቱ ፡ ቢቀና ፤ ወይም ፡ እርስዋ ፡ ሳትረክስ ፡ የቅንዓት ፡ መንፈስ ፡ ቢመጣበት ፥ ስለ ፡ ሚስቱም ፡ ቢቀና ፤ ፲፭ ያ ፡ ሰው ፡ ሚስቱን ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ያምጣት ፥ የኢፍ ፡ መስፈሪያም ፡ አሥረኛ ፡ እጅ ፡ ገብስ ፡ ዱቄት ፡ ቍርባን ፡ ስለ ፡ እርስዋ ፡ ያምጣ ፤ የቅንዓት ፡ ቍርባን ፡ ነውና ፥ ኃጢአትንም ፡ የሚያሳስብ ፡ የመታሰቢያ ፡ ቍርባን ፡ ነውና ፡ ዘይት ፡ አያፍስስበት ፥ ዕጣንም ፡ አይጨምርበት ።

፲፮ ካህኑም ፡ ያቀርባታል ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ያቆማታል ፤ ፲፯ ካህኑም ፡ የተቀደሰ ፡ ውኃ ፡ በሸክላ ፡ ዕቃ ፡ ይወስዳል ፤ ካህኑም ፡ በማደሪያው ፡ ውስጥ ፡ ካለው ፡ ትቢያ ፡ ወስዶ ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡ ይረጨዋል ፤ ፲፰ ካህኑም ፡ ሴቲቱን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያቆማታል ፥ የሴቲቱንም ፡ ራስ ፡ ይገልጣል ፥ በእጅዋም ፡ ለመታሰቢያ ፡ የሚሆነውን ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፥ ለቅንዓት ፡ ቍርባን ፥ ያኖራል ፤ በካህኑም ፡ እጅ ፡ እርግማን ፡ የሚያመጣው ፡ መራራ ፡ ውኃ ፡ ይሆናል ። ፲፱ ካህኑም ፡ ያምላታል ፥ ሴቲቱንም ፡ እንዲህ ፡ ይላታል ፦— ሌላ ፡ ወንድ ፡ አልተኛሽ ፥ በልሽ

ንም ፡ አልተውሽ ፥ ራስሽንም ፡ አላረከስሽ ፡
እንደ ፡ ሆነ ፥ እርግማንን ፡ ከሚያመጣ ፡ ከዚህ ፡
፳ መራራ ፡ ውኃ ፡ ንጹሕ ፡ ሁኚ ። ነገር ፡ ግን ፡ በል
ሽን ፡ ትተሽ ፡ ረክስሽ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ከባልሽም ፡
ሌላ ፡ ከወንድ ፡ ጋር ፡ ተኝተሽ ፡ እንደ ፡ ሆነ ።
፳፩ ካህኑም ፡ ሴቲቱን ፡ በመርገም ፡ መሐላ ፡ ያምላ
ታል ፥ ካህኑም ፡ ሴቲቱን ፦ እግዚአብሔር ፡
ጭንሽን ፡ እያሰለሰ ፡ ሆድሽንም ፡ እየነፋ ፥ እግ
ዚአብሔር ፡ ለመርገምና ፡ ለመሐላ ፡ በሕዝብሽ ፡
፳፪ መካከል ፡ ያድርግሽ ። እርግማንንም ፡ የሚያ
መጣ ፡ ይህ ፡ ውኃ ፡ ወደ ፡ ሆድሽ ፡ ይግባ ፥ ሆድሽ
ንም ፡ ይንፋው ፥ ጭንሽንም ፡ ያበስብሰው ፡ ይላ
ታል ። ሴቲቱም ፦ አሜን ፡ አሜን ፡ ትላለች ።
፳፫ ካህኑም ፡ እነዚህን ፡ መርገሞች ፡ በሰሌዳ ፡ ይጽ
ፈዋል ፥ በመራራውም ፡ ውኃ ፡ ይደመስሰዋል ።
፳፬ እርግማን ፡ የሚያመጣውንም ፡ መራራ ፡ ውኃ ፡
ለሴቲቱ ፡ ያጠጣታል ። የእርግማኑም ፡ ውኃ ፡
፳፭ በገባበት ፡ ጊዜ ፡ መራራ ፡ ይሆናል ። ካህኑም ፡
የቅንዓቱን ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ከሴቲቱ ፡ እጅ ፡
ይወስዳል ፥ የእህሉንም ፡ ቍርባን ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ፊት ፡ ይወዘውዘዋል ፥ ወደ ፡ መሠዊያ
፳፮ ውም ፡ ያመጣዋል ። ካህኑም ፡ ከእህሉ ፡ ቍር
ባን ፡ አንድ ፡ እፍኝ ፡ ሙሉ ፡ ለመታሰቢያው ፡
ወስዶ ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያቃጥለዋል ፥ ከዚ
ያም ፡ በኋላ ፡ ለሴቲቱ ፡ ውኃውን ፡ ያጠጣታል ።
፳፯ ውኃውን ፡ ከጠጣች ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ።
ረክሳና ፡ በባልዋ ፡ ላይ ፡ አመንዝራ ፡ እንደ ፡
ሆነች ፥ እርግማንን ፡ የሚያመጣው ፡ ውኃ ፡
ገብቶ ፡ መራራ ፡ ይሆንባታል ፥ ሆድዋም ፡ ይነ
ፋል ፥ ጭንዋም ፡ ይሰለስላል ። ሴቲቱም ፡ በሕዝ
፳፰ ብዋ ፡ መካከል ፡ ለመርገም ፡ ትሆናለች ። ያልረ
ከሰች ፡ ያለ ፡ ነውርም ፡ እንደ ፡ ሆነች ፥ ንጹሕ ፡
ትሆናለች ፥ ልጆችንም ፡ ታረግዛለች ።
፳፱ ፡ ፴ ሴት ፡ በልዋን ፡ ትታ ፡ በረከሰች ፡ ጊዜ ፥
ወይም ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ የቅንዓት ፡ መንፈስ ፡ በመ
ጣበት ፡ ጊዜ ፥ ስለ ፡ ሚስቱም ፡ በቀና ፡ ጊዜ ፥
የቅንዓት ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ። ሴቲቱንም ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያቈማት ፥ ካህኑም ፡ እንደ
፴፩ ዚህ ፡ ሕግ ፡ ሁሉ ፡ ያድርግባት ። ሰውዮውም ፡
ከኃጢአት ፡ ንጹሕ ፡ ይሆናል ፥ ሴቲቱም ፡ ኃጢ
አትዋን ፡ ትሸከማለች ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪ ተናገረው ፦ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ንገራ
ቸው ፦ ሰው ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ራሱን ፡ የተለየ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ የናዝራዊነት ፡
፫ ስእለት ፡ ቢሳል ፥ ከወይን ፡ ጠጅና ፡ ከሚያሰክር ፡
መጠጥ ፡ ራሱን ፡ የተለየ ፡ ያድርግ ። ከወይን ፡
ወይም ፡ ከሌላ ፡ ነገር ፡ የሚገኘውን ፡ ሆምጣጤ ፡
አይጠጣ ፥ የወይንም ፡ ጭማቂ ፡ አይጠጣ ። የወ
፬ ይን ፡ እሸት ፡ ወይም ፡ ዘቢብ ፡ አይብላ ። ራሱን ፡
የተለየ ፡ በደረገበት ፡ ወራት ፡ ሁሉ ፡ ከወይን ፡
የሆነውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ከውስጡ ፡ ፍሬ ፡ ጀምሮ ፡
እስከ ፡ ገፈፎው ፡ ድረስ ፡ አይብላ ።
፭ ራሱን ፡ ለመለየት ፡ ስእለት ፡ በደረገበት ፡
ወራት ፡ ሁሉ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ምላጭ ፡ አይደር
ስም ። ለእግዚአብሔር ፡ የተለየበት ፡ ወራት ፡
እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ የተቀደሰ ፡ ይሆናል ፥ የራ
ሱንም ፡ ጠጕር ፡ ያሳድጋል ።
፮ ለእግዚአብሔር ፡ ራሱን ፡ የተለየ ፡ በደረገ
በት ፡ ወራት ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ሬሳ ፡ አይቅረብ ።
፯ ለአምላኩ ፡ ያደረገው ፡ ስእለት ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡
ነውና ፡ አባቱ ፡ ወይም ፡ እናቱ ፡ ወይም ፡ ወን
ድሙ ፡ ወይም ፡ እኅቱ ፡ ሲሞቱ ፡ ሰውነቱን ፡ አያ
፰ ርክስበቸው ። ራሱን ፡ የተለየ ፡ በደረገበት ፡
ወራት ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ ፡
ነው ።
፱ ሰውም ፡ በአጠገቡ ፡ ድንገት ፡ ቢሞት ፡ የተ
ለየውንም ፡ ራሱን ፡ ቢያረክስ ፥ እርሱ ፡ በሚነጻ
በት ፡ ቀን ፡ ራሱን ፡ ይላጭ ። በሰባተኛው ፡ ቀን ፡
፲ ይላጨው ። በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ ሁለት ፡
ዋኖሶች ፡ ወይም ፡ ሁለት ፡ የርግብ ፡ ግልገሎች ፡
ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡
፲፩ ያምጣ ። ካህኑም ፡ አንዱን ፡ ለኃጢአት ፡ መሥ
ዋዕት ፡ ሁለተኛውንም ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ያቀርበዋል ። በሬሳም ፡ የተነሣ ፡ ኃጢአት ፡
ሠርቶአልና ፡ ያስተሰርይለታል ፥ በዚያም ፡ ቀን ፡
፲፪ ራሱን ፡ ይቀድሰዋል ። ራሱን ፡ የተለየ ፡ ያደረ
ገበትን ፡ ወራትም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይቀድ
ሳል ፥ የአንድ ፡ ዓመትም ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፡ ለበ
ደል ፡ መሥዋዕት ፡ ያምጣ ። ናዝራዊነቱ ፡ ግን ፡
ረክሶአልና ፡ ያለፈው ፡ ወራት ፡ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡
ይሆናል ።
፲፫ የመለየቱ ፡ ወራት ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ የናዝ
ራዊው ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ። ወደ ፡ መገናኛው ፡
፲፬ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ይቅረብ ። ቍርበኑንም ፡ ለእግ
ዚአብሔር ፡ ያቅርብ ። ነውር ፡ የሌለበት ፡ የአ
ንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፡ ለሚቃጠል ፡
መሥዋዕት ፥ ነውርም ፡ የሌለበትን ፡ የአንድ ፡
ዓመት ፡ እንስት ፡ ጠቦት ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋ
ዕት ፥ ነውርም ፡ የሌለበትን ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ለደ
፲፭ ኅንነት ፡ መሥዋዕት ፥ አንድ ፡ ሌማትም ፡ ቂጣ ፡
እንጀራ ፥ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ ከመልከም ፡ ዱቄ
ትም ፡ የተሠሩ ፡ እንጎቻዎች ፥ በዘይትም ፡ የተ
ቀባ ፡ ስስ ፡ ቂጣ ፥ የእህሉንም ፡ ቍርባን ፥ የመ
፲፮ ጠጡንም ፡ ቍርባን ፡ ያቅርብ ። ካህኑም ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያቀርበቸዋል ፥ የኃጢአቱ
ንም ፡ መሥዋዕት ፡ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋ
፲፯ ዕት ፡ ያሰርግለታል ። አውራውንም ፡ በግ ፡ ለደ
ኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ ከሌማቱ ፡ ቂጣ ፡ እንጀራ ፡
ጋር ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያቀርበል ። ካህኑም ፡
ደግሞ ፡ የእህሉን ፡ ቍርባንና ፡ የመጠጡን ፡
፲፰ ቍርባን ፡ ያቀርባል ። ናዝራዊውም ፡ የተለየ
ውን ፡ የራሱን ፡ ጠጕር ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡
አጠገብ ፡ ይላጫል ፥ የመለየቱንም ፡ ራስ ፡ ጠጕር ፡
ወስዶ ፡ ከደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ በታች ፡ ወዳ
፲፱ ለው ፡ እሳት ፡ ይጥለዋል ። ካህኑም ፡ የተቀቀለ

ውን ፡ የአውራውን ፡ በግ ፡ ወርች ፥ ከሌማቱም ፡ አንድ ፡ ቂጣ ፡ እንጐቻ ፡ አንድም ፡ ስስ ፡ ቂጣ ፡ ይወስዳል ፥ የተለየውንም ፡ የራስ ፡ ጠጕር ፡ ከተ ላጨ ፡ በኋላ ፡ በናዝራዊው ፡ እጆች ፡ ላይ ፡ ያኖ
፳ ራቸዋል ፤ ካህኑም ፡ እነዚህን ፡ ለመወዝወዝ ፡ ቍርባን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይወዘውዛ ቸዋል ፤ ይህም ፡ ከሚወዘወዘው ፡ ፍርምባና ፡ ከሚነሣው ፡ ወርች ፡ ጋር ፡ ለካህኑ ፡ የተቀደሰ ፡ ነው ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ናዝራዊው ፡ ወይን ፡ ይጠጣ ፡ ዘንድ ፡ ይችላል ።

፳፩ ስእለቱን ፡ የተሳለው ፡ የናዝራዊ ፥ እጁም ፡ ከሚያገኘው ፡ ሌላ ፡ ስለ ፡ ናዝራዊነቱ ፡ ለእግ ዚአብሔር ፡ የሚያቀርበው ፡ የቍርባኑ ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ስእለቱን ፡ እንደ ፡ ተሳለ ፡ እንደ ፡ ናዝራዊነቱ ፡ ሕግ ፡ እንዲሁ ፡ ያደርጋል ።

፳፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፳፫ ተናገረው ፡— ለአሮንና ፡ ለልጆቹ ፡ ንገራቸው ፡— የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ስትባርኩአቸው ፡ እን ዲህ ፡ በሉአቸው ፡ —

፳፬ እግዚአብሔር ፡ ይባርክህ ፥ ይጠብቅህም ፤

፳፭ እግዚአብሔር ፡ ፊቱን ፡ ያብራልህ ፥ ይራራ ልህም ፤

፳፮ እግዚአብሔር ፡ ፊቱን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ያንሣ ፥ ሰላምንም ፡ ይስጥህ ።

፳፯ እንዲሁ ፡ ስሜን ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ያደርጋሉ ፤ እኔም ፡ እባርካቸዋለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ሙሴ ፡ ማደሪያውን ፡ ፈጽሞ ፡ ከተከለ ፡ በኋላ ፥ እርሱንና ፡ ዕቃውን ፡ ሁሉ ፡ ከቀባና ፡ ከቀደሰ ፡ በኋላ ፥ መሠዊያውንና ፡ ዕቃ
፪ ውንም ፡ ሁሉ ፡ ከቀባና ፡ ከቀደሰ ፡ በኋላ ፤ የእ ስራኤል ፡ አለቆች ፥ የአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፥ ቍርባናቸውን ፡ አቀረቡ ፤ እነዚህም ፡ ከተቈጠሩት ፡ በላይ ፡ የተሾሙ ፡ የነገዶች ፡ አለ
፫ ቆች ፡ ነበሩ ። መባቸውንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አቀረቡ ፥ የተከደኑ ፡ ስድስት ፡ ሰረገሎች ፡ አሥራ ፡ ሁለትም ፡ በሬዎች ፤ በየሁለቱም ፡ አለ ቆች ፡ አንድ ፡ ሰረገላ ፡ አቀረቡ ፥ ሁሉም ፡ እያ ንዳንዱ ፡ አንድ ፡ በሬ ፡ በማደሪያው ፡ ፊት ፡
፬ አቀረቡ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡
፭ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ለመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ማገልገል ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ከእነርሱ ፡ ተቀብለህ ፡ ለሌዋውያን ፡ ለእያንዳንዱ ፡ እንደ ፡ አገልግሎ
፮ ታቸው ፡ ስጣቸው ። ሙሴም ፡ ሰረገሎችንና ፡ በሬዎችን ፡ ተቀብሎ ፡ ለሌዋውያን ፡ ሰጣቸው ።
፯ ለጌድሶን ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ አገልግሎታቸው ፡ ሁለት ፡ ሰረገሎችንና ፡ አራት ፡ በሬዎችን ፡ ሰጣ
፰ ቸው ። ከካህኑም ፡ ከአሮን ፡ ልጅ ፡ ከኢታምር ፡ እጅ ፡ በታች ፡ ላሉት ፡ ለሜራሪ ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ አገልግሎታቸው ፡ አራት ፡ ሰረገሎችንና ፡ ስም
፱ ንት ፡ በሬዎችን ፡ ሰጣቸው ። ለቀዓት ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ መቅደሱን ፡ ማገልገል ፡ የእነርሱ ፡ ነውና ፥ በትከሻቸውም ፡ ይሸከሙት ፡ ነበርና ፡ ምንም ፡ አልሰጣቸውም ።
፲ መሠዊያውም ፡ በተቀባ ፡ ቀን ፡ አለቆቹ ፡ መሠዊያውን ፡ ለመቀደስ ፡ ቍር ባንን ፡ አቀረቡ ፤ አለቆችም ፡ መባቸውን ፡ በመ
፲፩ ሠዊያው ፡ ፊት ፡ አቀረቡ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— አለቆቹ ፡ መሠዊያውን ፡ ለመቀደስ ፡ መባቸውን ፡ እያንዳንዱ ፡ በቀን ፡ በቀኑ ፡ ያቅ ርቡ ፡ አለው ።

፲፪ በመጀመሪያውም ፡ ቀን ፡ መባውን ፡ ያቀረበ ፡ ከይሁዳ ፡ ነገድ ፡ የአሚናዳብ ፡ ልጅ ፡ ነአሶን ፡
፲፫ ነበረ ። መባውም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ የተሞሉ ፥ ሚዛኑ ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ወጭት ፥ ሚዛኑም ፡ ሰባ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ድስት ፤ ዕጣንም ፡
፲፬ የተሞላ ፡ ሚዛኑ ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የወርቅ ፡ ጭልፋ ፤ ለሚቃጠልም ፡ መሥዋ
፲፭ ዕት ፡ አንድ ፡ ወይፈን ፥ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፥ አንድ ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፤ ለኃ
፲፮ ጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፤
፲፯ ለደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁለት ፡ በሬዎች ፥ አምስት ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ አምስት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፥ አምስት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነበረ ፤ የአሚናዳብ ፡ ልጅ ፡ የነአሶን ፡ መባ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፲፰ በሁለተኛውም ፡ ቀን ፡ የይሳኮር ፡ አለቃ ፡ የሶ
፲፱ ገር ፡ ልጅ ፡ ናትናኤል ፡ አቀረበ ። ለመባውም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መል ካም ፡ ዱቄት ፡ የተሞሉትን ፥ ሚዛኑ ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡ የሆነውን ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ወጭት ፥ ሚዛኑም ፡ ሰባ ፡ ሰቅል ፡ የሆነውን ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ድስት ፤
፳ ዕጣንም ፡ የተሞላውን ፡ ሚዛኑ ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡
፳፩ የሆነውን ፡ አንድ ፡ የወርቅ ፡ ጭልፋ ፤ ለሚቃ ጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ ወይፈን ፥ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፥ አንድ ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡
፳፪ ጠቦት ፤ ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡
፳፫ አውራ ፡ ፍየል ፤ ለደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁለት ፡ በሬዎች ፥ አምስት ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ አምስት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፥ አምስት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ አቀረበ ፤ የሶገር ፡ ልጅ ፡ የናትናኤል ፡ መባ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፳፬ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ የዛብሎን ፡ ልጆች ፡
፳፭ አለቃ ፡ የኬሎን ፡ ልጅ ፡ ኤልያብ ፤ መባውም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መል ካም ፡ ዱቄት ፡ የተሞሉ ፥ ሚዛኑ ፡ እንደ ፡ መቅ ደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ወጭት ፥ ሚዛኑም ፡ ሰባ ፡
፳፮ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ድስት ፤ ዕጣንም ፡ የተሞላ ፡ ሚዛኑ ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡
፳፯ የወርቅ ፡ ጭልፋ ፤ ለሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ ወይፈን ፥ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፥ አንድ ፡
፳፰ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፤ ለኃጢአ ትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፤
፳፱ ለደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁለት ፡ በሬዎች ፥

አምስት ፡ አውራ ፡ በጎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ÷ አምስት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነበረ ፤ የኬሎን ፡ ልጅ ፡ የኤልያብ ፡ መባ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፴ በአራተኛውም ፡ ቀን ፡ የሮቤል ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የሰዲዮር ፡ ልጅ ፡ ኤሊሱር ፤ ፴፩ መባውም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ የተሞሉ ÷ ሚዛኑ ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ወጭት ÷ ሚዛኑም ፡ ሰባ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ድስት ፤ ፴፪ ዕጣንም ፡ የተሞላ ፡ ሚዛኑ ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የወርቅ ፡ ጭልፋ ፤ ፴፫ ለሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ ወይፈን ÷ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ÷ አንድ ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፤ ፴፬ ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፤ ፴፭ ለደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁለት ፡ በሬዎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ በጎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ÷ አምስት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነበረ ፤ የሰዲዮር ፡ ልጅ ፡ የኤሊሱር ፡ መባ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፴፮ በአምስተኛውም ፡ ቀን ፡ የስምዖን ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የሱሪሰዳይ ፡ ልጅ ፡ ሰለሚኤል ፤ ፴፯ መባውም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ የተሞሉ ÷ ሚዛኑ ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ወጭት ÷ ሚዛኑም ፡ ሰባ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ድስት ፤ ፴፰ ዕጣንም ፡ የተሞላ ፡ ሚዛኑ ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የወርቅ ፡ ጭልፋ ፤ ፴፱ ለሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ ወይፈን ÷ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ÷ አንድ ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፤ ፵ ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፤ ፵፩ ለደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁለት ፡ በሬዎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ በጎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ÷ አምስት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነበረ ፤ የሱሪሰዳይ ፡ ልጅ ፡ የሰለሚኤል ፡ መባ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፵፪ በስድስተኛውም ፡ ቀን ፡ የጋድ ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የራጉኤል ፡ ልጅ ፡ ኤሊሳፍ ፤ ፵፫ መባውም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ የተሞሉ ÷ ሚዛኑ ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ወጭት ÷ ሚዛኑም ፡ ሰባ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ድስት ፤ ፵፬ ዕጣንም ፡ የተሞላ ፡ ሚዛኑ ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የወርቅ ፡ ጭልፋ ፤ ፵፭ ለሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ ወይፈን ÷ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ÷ አንድ ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፤ ፵፮ ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፤ ፵፯ ለደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁለት ፡ በሬዎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ በጎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ÷ አምስት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነበረ ፤ የራጉኤል ፡ ልጅ ፡ የኤሊሳፍ ፡ መባ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፵፰ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ የኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የዓሚሁድ ፡ ልጅ ፡ ኤሊሳማ ፤ ፵፱ መባውም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ የተሞሉ ÷ ሚዛኑ ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ወጭት ÷ ሚዛኑ ፡ ሰባ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ድስት ፤ ፶ ዕጣንም ፡ የተሞላ ፡ ሚዛኑ ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የወርቅ ፡ ጭልፋ ፤ ፶፩ ለሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ ወይፈን ÷ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ÷ አንድ ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፤ ፶፪ ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፤ ፶፫ ለደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁለት ፡ በሬዎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ በጎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ÷ አምስት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነበረ ፤ የዓሚሁድ ፡ ልጅ ፡ የኤሊሳማ ፡ መባ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፶፬ በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ የምናሴ ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የፍዳሱር ፡ ልጅ ፡ ገማልኤል ፤ ፶፭ መባውም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ የተሞሉ ÷ ሚዛኑ ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ወጭት ÷ ሚዛኑም ፡ ሰባ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ድስት ፤ ፶፮ ዕጣንም ፡ የተሞላ ፡ ሚዛኑ ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የወርቅ ፡ ጭልፋ ፤ ፶፯ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ ወይፈን ÷ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ÷ አንድ ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፤ ፶፰ ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፤ ፶፱ ለደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁለት ፡ በሬዎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ በጎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ÷ አምስት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነበረ ፤ የፍዳሱር ፡ ልጅ ፡ የገማልኤል ፡ መባ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፷ በዘጠኘኛውም ፡ ቀን ፡ የብንያም ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የጋዴዮን ፡ ልጅ ፡ አቢዳን ፤ ፷፩ መባውም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ የተሞሉ ÷ ሚዛኑ ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ወጭት ÷ ሚዛኑም ፡ ሰባ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ድስት ፤ ፷፪ ዕጣንም ፡ የተሞላ ፡ ሚዛኑ ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የወርቅ ፡ ጭልፋ ፤ ፷፫ ለሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ ወይፈን ÷ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ÷ አንድ ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፤ ፷፬ ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፤ ፷፭ ለደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁለት ፡ በሬዎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ በጎች ÷ አምስት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ÷ አምስት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነበረ ፤ የጋዴዮን ፡ ልጅ ፡ የአቢዳን ፡ መባ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፷፮ በአሥረኛውም ፡ ቀን ፡ የዳን ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የአሚሳዳይ ፡ ልጅ ፡ አኪዔዘር ፤ ፷፯ መባውም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መል

ከም ፡ ዱቄት ፡ የተሞሉ ፥ ሚዛኑ ፡ እንደ ፡ መቅ
ደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡
የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ወጭት ፥ ሚዛኑም ፡ ሰባ ፡
፷፰፤ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ድስት ፤ ዕጣንም ፡
የተሞላ ፡ ሚዛኑ ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡
፷፱፤ የወርቅ ፡ ጭልፋ ፤ ለሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡
አንድ ፡ ወይፈን ፥ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፥ አንድ ፡
፸፤ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፤ ለኃጢአትም ፡
፸፩፤ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፤ ለደኅንነ
ትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁለት ፡ በሬዎች ፥ አምስት ፡
አውራ ፡ በጎች ፥ አምስት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፥
አምስት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠበ
ቶች ፡ ነበረ ፤ የአሚሳዳይ ፡ ልጅ ፡ የአኪዔዘር ፡
መባ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፸፪፤ በአሥራ ፡ አንደኛውም ፡ ቀን ፡ የአሴር ፡
ልጆች ፡ አለቃ ፡ የኤክራን ፡ ልጅ ፡ ፋግኤል ፤
፸፫፤ መባውም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለ
ወሰ ፡ መልከም ፡ ዱቄት ፡ የተሞሉ ፥ ሚዛኑ ፡
እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡
ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ወጭት ፥ ሚዛኑም ፡
፸፬፤ ሰባ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ድስት ፤ ዕጣ
ንም ፡ የተሞላ ፡ ሚዛኑ ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡
፸፭፤ አንድ ፡ የወርቅ ፡ ጭልፋ ፤ ለሚቃጠልም ፡ መሥ
ዋዕት ፡ አንድ ፡ ወይፈን ፥ አንድ ፡ አውራ ፡
በግ ፥ አንድ ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፤
፸፮፤ ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡
፸፯፤ ፍየል ፤ ለደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁለት ፡
በሬዎች ፥ አምስት ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ አምስት ፡
አውራ ፡ ፍየሎች ፥ አምስት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡
ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነበረ ፤ የኤክራን ፡
ልጅ ፡ የፋግኤል ፡ መባ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፸፰፤ በአሥራ ፡ ሁለተኛውም ፡ ቀን ፡ የንፍታሌም ፡
፸፱፤ ልጆች ፡ አለቃ ፡ የዔናን ፡ ልጅ ፡ አኪሬ ፤ መባ
ውም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡
መልከም ፡ ዱቄት ፡ የተሞሉ ፥ ሚዛኑ ፡ እንደ ፡
መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፡
የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ወጭት ፥ ሚዛኑም ፡ ሰባ ፡
፹፤ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የብር ፡ ድስት ፤ ዕጣንም ፡
የተሞላ ፡ ሚዛኑ ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡
፹፩፤ የወርቅ ፡ ጭልፋ ፤ ለሚቃጠልም ፡ መሥዋ
ዕት ፡ አንድ ፡ ወይፈን ፥ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፥
፹፪፤ አንድ ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ ጠቦት ፤ ለኃ
ጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፤
፹፫፤ ለደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁለት ፡ በሬዎች ፥
አምስት ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ አምስት ፡ አውራ ፡
ፍየሎች ፥ አምስት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡
የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነበረ ፤ የዔናን ፡ ልጅ ፡ የአኪሬ ፡
መባ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፹፬፤ መሠዊያው ፡ በተቀባ ፡ ቀን ፡ የእስራኤል ፡
አለቆች ፡ ለመቀደሻው ፡ ያቀረቡት ፡ ቍርባን ፡
ይህ ፡ ነበረ ፤ አሥራ ፡ ሁለት ፡ የብር ፡ ወጭቶች ፥
አሥራ ፡ ሁለት ፡ የብር ፡ ድስቶች ፥ አሥራ ፡
፹፭፤ ሁለት ፡ የወርቅ ፡ ጭልፋዎች ፤ እያንዳንዱም ፡
የብር ፡ ወጭት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰቅል ፥ እያንዳ
ንዱም ፡ ድስት ፡ ሰባ ፡ ሰቅል ፡ ነበረ ፤ የዚህም ፡
ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ብር ፡ በመቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡
ሁለት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሰቅል ፡ ነበረ ።
፹፮፤ ዕጣንም ፡ የተሞሉ ፡ አሥራ ፡ ሁለቱ ፡ የወርቅ ፡
ጭልፋዎች ፥ እያንዳንዱ ፡ በመቅደሱ ፡ ሰቅል ፡
ሚዛን ፡ አሥር ፡ አሥር ፡ ሰቅል ፡ ነበረ ፤ የጭል
ፋዎቹ ፡ ወርቅ ፡ ሁሉ ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሰቅል ፡ ነበረ ።
፹፯፤ የሚቃጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ ከብት ፡ ሁሉ ፡ ከእ
ህሉ ፡ ቍርባን ፡ ጋር ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ወይፈ
ኖች ፥ አሥራ ፡ ሁለትም ፡ አውራ ፡ በጎች ፥
አሥራ ፡ ሁለትም ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡
ጠቦቶች ፡ ነበሩ ፤ የኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡
አውራ ፡ ፍየሎች ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ነበሩ ።
፹፰፤ የደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ከብት ፡ ሁሉ ፡ ሀያ ፡
አራት ፡ በሬዎች ፥ ስድሳም ፡ አውራ ፡ በጎች ፥
ስድሳም ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፥ ስድሳም ፡ የአ
ንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነበሩ ።
መሠዊያው ፡ ከተቀባ ፡ በኋላ ፡ ለመቀደሻው ፡
የቀረበ ፡ ቍርባን ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፹፱፤ ሙሴም ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ እር
ሱን ፡ ለመነጋገር ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ በምስክሩ ፡
ታቦት ፡ ላይ ፡ ካለው ፡ ከስርየት ፡ መክደኛ ፡
በላይ ፡ ከኪሩቤልም ፡ መካከል ፡ ድምፅ ፡ ሲና
ገረው ፡ ይሰማ ፡ ነበር ፤ እርሱም ፡ ይናገረው ፡
ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪፤ ተናገረው ፦ — መብራቶቹን ፡ ስትለኵስ ፡ ሰባቱ ፡
መብራቶች ፡ በመቅረዙ ፡ ፊት ፡ ያበራሉ ፡ ብለህ ፡
፫፤ ለአሮን ፡ ንገረው ። አሮንም ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ፤
እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘ ፡ በመቅረዙ ፡
፬፤ ፊት ፡ መብራቶቹን ፡ ለኰሰ ። መቅረዙም ፡ እን
ዲህ ፡ ሆኖ ፡ ተሠርቶ ፡ ነበር ፤ ከተቀጠቀጠ ፡
ወርቅ ፡ ተሠራ ፤ እስከ ፡ አገዳውና ፡ እስከ ፡ አበ
ቦቹ ፡ ድረስ ፡ ከተቀጠቀጠ ፡ ሥራ ፡ ነበረ ፤ እግ
ዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዳሳየው ፡ ምሳሌ ፡ መቅ
ረዙን ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ።

፭፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፮፤ ተናገረው ፦ — ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡
፯፤ ሌዋውያንን ፡ ወስደህ ፡ አንጻቸው ። ታነጻቸው ፡
ዘንድ ፡ እንዲህ ፡ ታደርግላቸዋለህ ፤ ኃጢአትን ፡
የሚያነጻውን ፡ ውኃ ፡ እርጫቸው ፥ በገላቸ
ውም ፡ ሁሉ ፡ ምላጭ ፡ ያሳልፉ ፥ ልብሳቸውንም ፡
፰፤ ይጠቡ ፥ ይታጠቡም ። ወይፈንን ፥ ለእህሉም ፡
ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልከም ፡ ዱቄ
ትን ፡ ይውሰዱ ፥ ሌላውንም ፡ ወይፈን ፡ ለኃጢ
፱፤ አት ፡ መሥዋዕት ፡ ውሰድ ። ሌዋውያንንም ፡
በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ፊት ፡ አቅርብ ፤ የእስ
ራኤልንም ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ሰብስብ ።
፲፤ ሌዋውያንንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አቅር
ባቸው ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በሌዋውያን ፡
፲፩፤ ላይ ፡ እጃቸውን ፡ ይጫኑባቸው ። አሮንም ፡
ሌዋውያን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡

ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ስጦታ ፡ አድ
ርጎ ÷ ሌዋውያንን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያቅ
፲፪ ርብ ። ሌዋውያኑም ፡ በወይፈኖቹ ፡ ራሶች ፡ ላይ ፡
እጆቻቸውን ፡ ይጫኑ ፤ ለሌዋውያንም ፡ ስለ ፡
ማስተስረያ ፡ አንዱን ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ÷
ሁለተኛውንም ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ለእ
፲፫ ግዚአብሔር ፡ አቅርብ ። ሌዋውያንንም ፡ በአ
ሮንና ፡ በልጆቹ ፡ ፊት ፡ አቁማቸው ÷ በእግዚአ
ብሔርም ፡ ፊት ፡ ስጦታ ፡ አድርገህ ፡ አቅርባ
፲፬ ቸው ። እንዲሁ ፡ ሌዋውያንን ፡ ከእስራኤል ፡
ልጆች ፡ መካከል ፡ ለይ ፤ ሌዋውያንም ፡ ለእኔ ፡
ይሁኑ ።

፲፭ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ሌዋውያን ፡ የመገናኛውን ፡
ድንኳን ፡ አገልግሎት ፡ ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡ ይገ
ባሉ ፤ ታነጻቸውማለህ ÷ ስጦታም ፡ አድርገህ ፡
፲፮ ታቀርባቸዋለህ ። እነርሱም ፡ ከእስራኤል ፡
ልጆች ፡ መካከል ፡ ፈጽሞ ፡ ለእኔ ፡ ተሰጥተዋ
ልና ፤ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በኵራት ፡ ሁሉ ÷
ማኅፀን ፡ በሚከፍት ፡ ሁሉ ፡ ፋንታ ፡ ለእኔ ፡ ወስ
፲፯ ጄአቸዋለሁ ። በግብፅ ፡ ምድር ፡ ያለውን ፡
በኵር ፡ ሁሉ ፡ በገደልሁበት ፡ ቀን ፡ የእስራኤ
ልን ፡ ልጆች ፡ በኵራት ፡ ሁሉ ÷ ሰው ፡ ወይም ፡
እንስሳ ÷ ለእኔ ፡ ቀድሼአቸዋለሁና ፡ የእኔ ፡ ናቸው ።
፲፰ በእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በኵራት ፡ ሁሉ ፡ ፋንታ ፡
፲፱ ሌዋውያንን ፡ ወስጄአለሁ ። የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ ወደ ፡ መቅደሱ ፡ በቀረቡ ፡ ጊዜ ፡ መቅ
ሠፍት ፡ እንዳያገኛቸው ÷ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ያስተሰርዩላቸው ፡ ዘንድ ÷ የእስራኤልንም ፡
ልጆች ፡ አገልግሎት ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡
ውስጥ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ሌዋውያንን ፡ ከእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ለአሮንና ፡ ለልጆቹ ፡
ስጦታ ፡ አድርጌ ፡ ሰጥቼአቸዋለሁ ።

፳ ሙሴና ፡ አሮን ፡ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ በሌዋውያን ፡ ላይ ፡
አደረጉ ፤ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ ስለ ፡ ሌዋ
ውያን ፡ እንዳዘዘው ፡ እንዲሁ ፡ የእስራኤል ፡
፳፩ ልጆች ፡ አደረጉላቸው ። ሌዋውያንም ፡ ከኃ
ጢአት ፡ ተጣጠቡ ÷ ልብሳቸውንም ፡ አጠቡ ፤
አሮንም ፡ ስጦታ ፡ አድርጎ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ አቀረባቸው ÷ አሮንም ፡ ያነጻቸው ፡ ዘንድ ፡
፳፪ አስተሰረየላቸው ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ሌዋው
ያን ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ በአሮ
ንና ፡ በልጆቹ ፡ ፊት ፡ አገልግሎታቸውን ፡ ይሠሩ ፡
ዘንድ ፡ ገቡ ፤ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ ስለ ፡
ሌዋውያን ፡ እንዳዘዘው ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉላ
ቸው ።

፳፫ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፳፬ ተናገረው ፡— የሌዋውያን ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ፤
ከሀያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡
በላይ ፡ ያሉት ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ሥራ ፡
፳፭ ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡ ይገባሉ ። ዕድሜአቸውም ፡
አምሳ ፡ ዓመት ፡ ሲሞላ ፡ የአገልግሎታቸውን ፡
ሥራ ፡ ይተዋሉ ÷ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ አይሠሩም ፤
፳፮ የተሰጣቸውን ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ወንድሞቻ
ቸውን ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ያገለ
ግላሉ ፤ የድንኳኑን ፡ አገልግሎት ፡ አይሠሩም ።
እንዲሁ ፡ ስለ ፡ ሥራቸው ፡ በሌዋውያን ፡ ላይ ፡
ታደርጋለህ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ከግብፅም ፡ ምድር ፡ በወጡ ፡ በሁለተኛው ፡
ዓመት ፡ በመጀመሪያው ፡ ወር ፡ በሲና ፡ ምድረ ፡
በዳ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪ ተናገረው ፡— የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በጊዜው ፡
፫ ፋሲካውን ፡ ያድርጉ ፤ በዚህ ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡
አራተኛው ፡ ቀን ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡ በጊዜው ፡ አድ
ርጉት ፤ እንደ ፡ ሥርዓቱ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ፍር
፬ ዱም ፡ ሁሉ ፡ አድርጉት ። ሙሴም ፡ ፋሲካን ፡
ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ተናገ
፭ ራቸው ። በመጀመሪያውም ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡
አራተኛው ፡ ቀን ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡ በሲና ፡ ምድረ ፡
በዳ ፡ ፋሲካን ፡ አደረጉ ፤ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡
እንዳዘዘው ፡ እንዲሁ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
፮ አደረጉ ። በሞተ ፡ ሰው ፡ ሬሳ ፡ የረከሱ ፡ ሰዎ
ችም ፡ ነበሩ ÷ ስለዚህም ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ፋሲካን ፡
ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉም ። በዚያም ፡ ቀን ፡
፯ ወደ ፡ ሙሴና ፡ ወደ ፡ አሮን ፡ ቀረቡ ። እነዚ
ያም ፡ ሰዎች ፡— በሞተ ፡ ሰው ፡ ሬሳ ፡ ረክሰናል ፤
በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ በጊዜው ፡ ቍር
ባን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እንዳናቀርብ ፡ ስለ ፡ ምን ፡
፰ እንከለከላለን ? አሉት ። ሙሴም ፡— እግዚአ
ብሔር ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ የሚያዝዘውን ፡ እስክ
ሰማ ፡ ድረስ ፡ ቈዩ ፡ አላቸው ።

፱ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፲ ተናገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡
ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— ከእናንተ ፡ ወይም ፡ ከት
ውልዶቻችሁ ፡ ዘንድ ፡ ሰው ፡ በሬሳ ፡ ቢረክስ ÷
ወይም ፡ ሩቅ ፡ መንገድ ፡ ቢሄድ ÷ እርሱ ፡ ደግሞ ፡
፲፩ ለእግዚአብሔር ፡ ፋሲካን ፡ ያድርግ ። በሁለተ
ኛው ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ በመሸ ፡
ጊዜ ፡ ያድርጉት ፤ ከቂጣ ፡ እንጀራና ፡ ከመራራ ፡
፲፪ ቅጠል ፡ ጋር ፡ ይብሉት ። ከእርሱም ፡ እስከ ፡
ነገ ፡ ምንም ፡ አያስቀሩ ÷ ከእርሱም ፡ አጥንትን ፡
አይስበሩ ፤ እንደ ፡ ፋሲካ ፡ ሥርዓት ፡ ሁሉ ፡ ያድ
፲፫ ርጉት ። ነገር ፡ ግን ፡ ንጹሕ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ በመ
ንገድም ፡ ላይ ፡ ያልሆነ ፡ ፋሲካን ፡ ባያደርግ ÷
ያ ፡ ሰው ፡ ከሕዝቡ ፡ ዘንድ ፡ ተለይቶ ፡ ይጠፋል ፤
የእግዚአብሔርን ፡ ቍርባን ፡ በጊዜው ፡ አላቀ
ረበምና ፡ ያ ፡ ሰው ፡ ኃጢአቱን ፡ ይሸከማል ።
፲፬ በመካከላችሁም ፡ መጻተኛ ፡ ቢኖር ÷ ለእግዚአ
ብሔር ፡ ፋሲካን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ቢወድድ ÷
እንደ ፡ ፋሲካ ፡ ሥርዓት ፡ እንደ ፡ ፍርዱም ፡ እን
ዲሁ ፡ ያድርግ ፤ ለመጻተኛና ፡ ለአገር ፡ ልጅ ፡
አንድ ፡ ሥርዓት ፡ ይሁንላችሁ ።

፲፭ ማደሪያውም ፡ በተተከለ ፡ ቀን ፡ ደመናው ፡
የምስክሩን ፡ ድንኳን ፡ ሸፈነው ፤ ከማታም ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ጥዋት ፡ ድረስ ፡ በማደሪያው ፡
፲፮ ላይ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ይመስል ፡ ነበር ። እንዲሁ ፡

ሁልጊዜ ፡ ነበረ ፤ በቀን ፡ ደመና ፡ በሌሊትም ፡
**፲፯** የእሳት ፡ አምሳል ፡ ይሸፍነው ፡ ነበር ። ደመና
ውም ፡ ከድንኳኑ ፡ ላይ ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ በዚያን ፡
ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ይጓዙ ፡ ነበር ፤ ደመና
ውም ፡ በቆመበት ፡ ስፍራ ፡ በዚያ ፡ የእስራኤል ፡
**፲፰** ልጆች ፡ ይሰፍሩ ፡ ነበር ። በእግዚአብሔር ፡
ትእዛዝ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ይጓዙ ፡ ነበር ÷
በእግዚአብሔርም ፡ ትእዛዝ ፡ ይሰፍሩ ፡ ነበር ፤
ደመናው ፡ በማደሪያው ፡ ላይ ፡ በተቀመጠበት ፡
ዘመን ፡ ሁሉ ፡ በሰፈራቸው ፡ ይቀመጡ ፡ ነበር ።
**፲፱** ደመናውም ፡ በማደሪያው ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡
በተቀመጠ ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የእግ
ዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ይጠብቁ ፡ ነበር ÷ አይጓ
**፳** ዙምም ፡ ነበር ። አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ደመናው ፡
ጥቂት ፡ ቀን ፡ በማደሪያው ፡ ላይ ፡ ይሆን ፡ ነበር ፤
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡
በሰፈራቸው ፡ ይቀመጡ ፡ ነበር ፤ እንደ ፡ እግዚ
**፳፩** አብሔርም ፡ ትእዛዝ ፡ ይጓዙ ፡ ነበር ። አንዳ
ንድ ፡ ጊዜም ፡ ደመናው ፡ ከማታ ፡ ጀምሮ ፡
እስከ ፡ ጥዋት ፡ ድረስ ፡ ይቀመጥ ፡ ነበር ፤ በጥዋ
ትም ፡ ደመናው ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ ይጓዙ ፡ ነበር ፤
በቀንም ፡ በሌሊትም ፡ ቢሆን ÷ ደመናው ፡ በተ
**፳፪** ነሣ ፡ ጊዜ ፡ ይጓዙ ፡ ነበር ። ደመናውም ፡ ሁለት ፡
ቀን ፡ ወይም ፡ አንድ ፡ ወር ፡ ወይም ፡ አንድ ፡
ዓመት ፡ ቆይቶ ፡ በማደሪያው ፡ ላይ ፡ ቢቀመጥ ፡
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በሰፈራቸው ፡ ይቀመጡ ፡
ነበር ÷ አይጓዙምም ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በተ
**፳፫** ነሣ ፡ ጊዜ ፡ ይጓዙ ፡ ነበር ። በእግዚአብሔር ፡
ትእዛዝ ፡ ይሰፍሩ ፡ ነበር ÷ በእግዚአብሔርም ፡
ትእዛዝ ፡ ይጓዙ ፡ ነበር ÷ እግዚአብሔር ፡
በሙሴ ፡ እጅ ፡ እንዳዘዘ ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ትእዛዝ ፡ ይጠብቁ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

**፩** እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
**፪** ተናገረው ፡— ሁለት ፡ የብር ፡ መለከቶች ፡ አጠ
ፍጥፈህ ፡ ለአንተ ፡ አድርግ ፤ ማኅበሩን ፡ ለመጥ
ራት ፡ ከሰፈራቸውም ፡ ለማስጓዝ ፡ ይሁኑልህ ።
**፫** ሁለቱም ፡ መለከቶች ፡ በተነፉ ፡ ጊዜ ፡ ማኅበሩ ፡
ሁሉ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡
**፬** ደጃፍ ፡ ይሰብሰቡ ። አንድ ፡ መለከት ፡ ሲነፉ ፡
ታላላቆቹ ፡ የእስራኤል ፡ አእላፍ ፡ አለቆች ፡ ወደ ፡
**፭** አንተ ፡ ይሰብሰቡ ። መለከትንም ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡
ድምፅ ፡ ስትነፉ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ የሰፈ
**፮** ሩት ፡ ይጓዙ ። ሁለተኛውንም ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡
ድምፅ ፡ ስትነፉ ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ የሰፈሩት ፡
**፯** ይጓዙ ፤ ለማስጓዝ ፡ መለከትን ፡ ይነፉሉ ። ጉባ
ኤውም ፡ በሚሰበሰብበት ፡ ጊዜ ፡ ንፉ ÷ ነገር ፡
**፰** ግን ፡ ድምፁን ፡ ከፍ ፡ አታድርጉት ። የአሮንም ፡
ልጆች ፡ ካህናቱ ፡ መለከቶቹን ፡ ይንፉ ፤ እነር
ሱም ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ ለዘላለም ፡ ሥርዓት ፡
**፱** ይሁኑ ። በሚገፋችሁም ፡ ጠላት ፡ ላይ ፡ በምድ
ራችሁ ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ ስትወጡ ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡
ድምፅ ፡ መለከቶቹን ፡ ንፉ ፤ በእግዚአብሔርም ፡
በአምላካችሁ ፡ ፊት ፡ ትታሰባላችሁ ÷ ከጠላ
**፲** ቶቻችሁም ፡ ትድናላችሁ ። ደግሞ ፡ በደስታ
ችሁ ፡ ቀን ÷ በበዓላታችሁም ፡ ዘመን ÷ በወርም ፡
መባቻ ÷ በሚቃጠል ፡ መሥዋዕታችሁና ፡ በደ
ኅንነት ፡ መሥዋዕታችሁ ፡ ላይ ፡ መለከቶቹን ፡
ንፉ ፤ እነርሱም ፡ በአምላካችሁ ፡ ፊት ፡ ለመታ
ሰቢያ ፡ ይሆኑላችኋል ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡
አምላካችሁ ፡ ነኝ ።

**፲፩** በሁለተኛውም ፡ ዓመት ፡ በሁለተኛው ፡ ወር ፡
ከወሩም ፡ በሀያኛው ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ ደመ
**፲፪** ናው ፡ ከምስክሩ ፡ ማደሪያ ፡ ላይ ፡ ተነሣ ። የእ
ስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከሲና ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
በየጕዞአቸው ፡ ተጓዙ ፤ ደመናውም ፡ በፋራን ፡
**፲፫** ምድረ ፡ በዳ ፡ ቆመ ። በመጀመሪያም ፡ እግዚ
አብሔር ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ እንዳዘዘ ፡ ተጓዙ ።
**፲፬** በመጀመሪያም ፡ የይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ሰፈር ፡
ዓላማ ፡ በየሠራዊታቸው ፡ ተጓዘ ፤ በሠራዊ
ቱም ፡ ላይ ፡ የአሚናዳብ ፡ ልጅ ፡ ነአሶን ፡ አለቃ ፡
**፲፭** ነበረ ። በይሳኮርም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ሠራዊት ፡
ላይ ፡ የሶገር ፡ ልጅ ፡ ናትናኤል ፡ አለቃ ፡ ነበረ ።
**፲፮** በዛብሎንም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ሠራዊት ፡ ላይ ፡
የኬሎን ፡ ልጅ ፡ ኤልያብ ፡ አለቃ ፡ ነበረ ።

**፲፯** ማደሪያውም ፡ ተነቀለ ፤ ማደሪያውንም ፡ የተ
ሸከሙ ፡ የጌድሶን ፡ ልጆችና ፡ የሜራሪ ፡ ልጆች ፡
**፲፰** ተጓዙ ። የሮቤልም ፡ ሰፈር ፡ ዓላማ ፡ በየሠራዊ
ታቸው ፡ ተጓዘ ፤ በሠራዊቱም ፡ ላይ ፡ የሰዲዮር ፡
**፲፱** ልጅ ፡ ኤሊሱር ፡ አለቃ ፡ ነበረ ። በስምዖንም ፡
ልጆች ፡ ነገድ ፡ ሠራዊት ፡ ላይ ፡ የሱሪሰዳይ ፡
**፳** ልጅ ፡ ሰለሚኤል ፡ አለቃ ፡ ነበረ ። በጋድም ፡
ልጆች ፡ ነገድ ፡ ሠራዊት ፡ ላይ ፡ የራጉኤል ፡
ልጅ ፡ ኤሊሳፍ ፡ አለቃ ፡ ነበረ ።

**፳፩** ቀዓታውያንም ፡ መቅደሱን ፡ ተሸክመው ፡
ተጓዙ ፤ እነዚህም ፡ እስኪመጡ ፡ ድረስ ፡ እነዚያ ፡
**፳፪** ማደሪያውን ፡ ተከሉ ። የኤፍሬምም ፡ ልጆች ፡
ሰፈር ፡ ዓላማ ፡ በየሠራዊታቸው ፡ ተጓዘ ፤ በሠ
ራዊቱም ፡ ላይ ፡ የዓሚሁድ ፡ ልጅ ፡ ኤሊሳማ ፡
**፳፫** አለቃ ፡ ነበረ ። በምናሴም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡
ሠራዊት ፡ ላይ ፡ የፍዳሱር ፡ ልጅ ፡ ገማልኤል ፡
**፳፬** አለቃ ፡ ነበረ ። በብንያምም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡
ሠራዊት ፡ ላይ ፡ የጋዴዮን ፡ ልጅ ፡ አቢዳን ፡
አለቃ ፡ ነበረ ።

**፳፭** ከሰፈሮቹ ፡ ሁሉ ፡ በኋላ ፡ የሆነ ፡ የዳን ፡ ልጆች ፡
ሰፈር ፡ ዓላማ ፡ በየሠራዊታቸው ፡ ተጓዘ ፤ በሠ
ራዊቱም ፡ ላይ ፡ የአሚሳዳይ ፡ ልጅ ፡ አኪዔዘር ፡
**፳፮** አለቃ ፡ ነበረ ። በአሴርም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡
ሠራዊት ፡ ላይ ፡ የኤክራን ፡ ልጅ ፡ ፋግኤል ፡
**፳፯** አለቃ ፡ ነበረ ። በንፍታሌምም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡
ሠራዊት ፡ ላይ ፡ የዔናን ፡ ልጅ ፡ አኪሬ ፡ አለቃ ፡
**፳፰** ነበረ ። እንዲሁ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ጕዞ ፡
በየሠራዊታቸው ፡ ነበረ ፤ እነርሱም ፡ ተጓዙ ።
**፳፱** ሙሴም ፡ የሚስቱን ፡ አባት ፡ የምድያማዊ
ውን ፡ የራጉኤልን ፡ ልጅ ፡ ኦባብን ፡— እግዚአ
ብሔር ፡— ለእናንተ ፡ እሰጠዋለሁ ፡ ወዳለው ፡
ስፍራ ፡ እንሄዳለን ፤ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ እስ

ራኤል ፡ መልካምን ፡ ነገር ፡ ተናግሮአልና ፡
አንተ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ና ÷ መልካምን ፡ እናደር
፴ ግልሃለን ፡ አለው ። እርሱም ፡— አልሄድም ÷
ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ አገሬና ፡ ወደ ፡ ዘመዶቼ ፡ እሄ
፴፩ ዳለሁ ፡ አለው ። እርሱም ፡— እባክህ ÷ በም
ድረ ፡ በዳ ፡ የምንሰፍርበትን ፡ አንተ ፡ ታውቃ
ለህና ÷ እንደ ፡ ዓይኖቻችንም ፡ ትሆንልናለህና ፡
፴፪ አትተወን ፤ ከእኛም ፡ ጋር ፡ ብትሄድ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ከሚያደርግልን ፡ መልካም ፡ ነገር ፡
ሁሉ ፡ እኛ ፡ ለአንተ ፡ እናደርጋለን ፡ አለ ።
፴፫ ከእግዚአብሔርም ፡ ተራራ ፡ የሦስት ፡ ቀን ፡
መንገድ ፡ ያህል ፡ ተጓዙ ፤ የእግዚአብሔርም ፡
የኪዳኑ ፡ ታቦት ፡ የሚያድርበትን ፡ ስፍራ ፡ ይፈ
ልግላቸው ፡ ዘንድ ፡ የሦስት ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡
፴፬ ቀደማቸው ። ከሰፈራቸውም ፡ በተጓዙ ፡ ጊዜ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ደመና ፡ ቀን ፡ ቀን ፡ በላያቸው ፡
ነበረ ።
፴፭ ሙሴም ፡ ታቦቱ ፡ በተጓዘ ፡ ጊዜ ፡— አቤቱ ÷
ተነሣ ÷ ጠላቶችህም ፡ ይበተኑ ÷ የሚጠሉህም ፡
፴፮ ከፊትህ ፡ ይሽሹ ፡ ይል ፡ ነበር ። በረፈም ፡
ጊዜ ፡— አቤቱ ÷ ወደ ፡ እስራኤል ፡ አልፍ ፡ አእ
ላፋት ፡ ተመለስ ፡ ይል ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ሕዝቡም ፡ ክፉ ፡ ሆነው ፡ በእግዚአብሔር ፡
ላይ ፡ አጕረመረሙ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ሰምቶ ፡
ተቈጣ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ እሳት ፡ በመከከላ
፪ ቸው ፡ ነደደች ÷ የሰፈሩንም ፡ ዳር ፡ በላች ። ሕዝ
ቡም ፡ ወደ ፡ ሙሴ ፡ ጮኹ ፤ ሙሴም ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ጸለየ ÷ እሳቲቱም ፡ ጠፋች ።
፫ የእግዚአብሔርም ፡ እሳት ፡ በመከከላቸው ፡ ስለ ፡
ነደደች ፡ የዚያን ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ ተቤራ ፡ ብሎ ፡
ጠራው ።
፬ በመከከላቸውም ፡ የነበሩ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ሕዝብ ፡
እጅግ ፡ ጐመጁ ፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ደግሞ ፡
ያለቅሱ ፡ ነበር ፡— የምንበላውን ፡ ሥጋ ፡ ማን ፡
፭ ይሰጠናል ? በግብፅ ፡ ያለ ፡ ዋጋ ፡ እንበላው ፡
የነበረውን ፡ ዓሣ ÷ ዱባውንም ÷ በጢኹንም ÷
ኩራቱንም ÷ ቀዩንም ፡ ሽንኩርት ÷ ነጩንም ፡
፮ ሽንኩርት ፡ እናስባለን ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ሰውነታ
ችን ፡ ደረቀች ፤ ዓይናችንም ፡ ከዚህ ፡ መና ፡
፯ በቀር ፡ ምንም ፡ አታይም ፡ አሉ ። መናውም ፡
እንደ ፡ ድንብላል ፡ ዘር ፡ ነበረ ÷ መልኩም ፡
፰ ሙጫ ፡ ይመስል ፡ ነበር ። ሕዝቡም ፡ እየዞሩ ፡
ይለቅሙ ፡ ነበር ÷ በወፍጮም ፡ ይፈጩት ÷
ወይም ፡ በሙቀጫ ፡ ይወቅጡት ÷ በምንቸትም ፡
ይቀቅሉት ፡ ነበር ÷ እንጐቻም ፡ ያደርጉት ፡ ነበር ፤
ጣዕሙም ፡ በዘይት ፡ እንደ ፡ ተለወሰ ፡ እንጐቻ ፡
፱ ነበረ ። ሌሊትም ፡ ጠል ፡ በሰፈሩ ፡ ላይ ፡ በወ
ረደ ፡ ጊዜ ፡ መናው ፡ በላዩ ፡ ይወርድ ፡ ነበር ።
፲ ሙሴም ፡ ሕዝቡ ፡ በወገኖቻቸው ÷ ሰው ፡
ሁሉ ፡ በድንኳኑ ፡ ደጃፍ ÷ ሲያለቅሱ ፡ ሰማ ፤
የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ እጅግ ፡ ነደደ ፤
፲፩ ሙሴም ፡ ተቈጣ ። ሙሴም ፡ እግዚአብሔርን ፡
አለው ፡— ለምን ፡ በባሪያህ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ አደረ
ግህ ? ለምንስ ፡ በፊትህ ፡ ሞገስ ፡ አላገኘሁም ?
ለምንስ ፡ የዚህን ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ሸክም ፡ በእኔ ፡
፲፪ ላይ ፡ አደረግህ ? አንተ ፡ ለአባቶቻቸው ፡ ወደ ፡
ማልህላቸው ፡ ምድር ፡ አደርሳቸው ፡ ዘንድ ፡—
ሞግዚት ፡ የሚጠባውን ፡ ልጅ ፡ እንድታቅፍ ፡
በብብትህ ፡ እቀፋቸው ፡ የምትለኝ ÷ በውኑ ፡
ይህን ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ እኔ ፡ ፀንስሁትን ? ወለድሁ
፲፫ ትንስ ? በፊቴ ፡ ያለቅሳሉና ፡— የምንበላውን ፡
ሥጋ ፡ ስጠን ፡ ይላሉና ፡ ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡
የምሰጠው ፡ ሥጋ ፡ ከወዴት ፡ እወስዳለሁ ?
፲፬ እጅግ ፡ ከብዶኛልና ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ሕዝብ ፡ ልሸ
፲፭ ክም ፡ አልችልም ። እንዲህስ ፡ ከምታደርግ
ብኝ ÷ በፊትህ ፡ ሞገስ ፡ አግኝቼ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷
በእኔ ፡ ላይ ፡ የሚሆነውን ፡ መከራ ፡ እንዳላይ ÷
እባክህ ÷ ፈጽሞ ፡ ግደለኝ ።
፲፮ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— ከእስ
ራኤል ፡ ሽማግሌዎች ÷ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ሽማግ
ሌዎችና ፡ አለቆች ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ የምታውቃ
ቸውን ÷ ሰባ ፡ ሰዎች ፡ ሰብስብልኝ ÷ ወደ ፡ መገ
ናኛውም ፡ ድንኳን ፡ አምጣቸው ÷ በዚያም ፡
፲፯ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አቁማቸው ። እኔም ፡ እወርዳ
ለሁ ÷ በዚያም ፡ እነጋገርሃለሁ ÷ በአንተ ፡ ካለ
ውም ፡ መንፈስ ፡ ወስጄ ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ አደ
ርገዋለሁ ፤ አንተም ፡ ብቻ ፡ እንዳትሸከም ፡ የሕ
ዝቡን ፡ ሸክም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይሸከማሉ ።
፲፰ ሕዝቡንም ፡ በላቸው ፡— የምንበላውን ፡ ሥጋ ፡
ማን ፡ ይሰጠናል ? በግብፅ ፡ ደኅና ፡ ነበረልን ፡
እያላችሁ ፡ ያለቀሳችሁት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ጆሮ ፡ ደርሶአልና ፡ ለነገ ፡ ተቀደሱ ÷ ሥጋንም ፡
ትበላላችሁ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ሥጋን ፡ ይሰጣ
፲፱ ችኋል ÷ ትበሉማላችሁ ። አንድ ፡ ቀን ፡ ወይም ፡
ሁለት ፡ ቀን ፡ ወይም ፡ አምስት ፡ ቀን ፡ ወይም ፡
አሥር ፡ ቀን ፡ ወይም ፡ ሀያ ፡ ቀን ፡ አትበሉም ፤
፳ ነገር ፡ ግን ፡ በመከከላችሁ ፡ ያለውን ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ ንቃችኋልና ÷ በፊቱም ፡— ለምን ፡ ከግ
ብፅ ፡ ወጣን ? ብላችሁ ፡ አልቀሳችኋልና ፡ በአፍን
ጫችሁ ፡ እስኪወጣ ፡ እስኪሰለቻችሁም ፡ ድረስ ፡
፳፩ ወር ፡ ሙሉ ፡ ትበሉታላችሁ ። ሙሴም ፡—
እኔ ፡ በመከከላቸው ፡ ያለሁ ፡ ሕዝብ ፡ ስድስት ፡
መቶ ፡ ሺህ ፡ እግረኛ ፡ ናቸው ፤ አንተም ፡— ወር ፡
ሙሉ ፡ የሚበሉትን ፡ ሥጋ ፡ እኔ ፡ እሰጣቸዋለሁ ፡
፳፪ አልህ ። እነርሱን ፡ የሚያጠግብ ፡ የበሬና ፡ የበግ ፡
መንጋ ፡ ይታረድን ? ወይስ ፡ የባሕር ፡ ዓሣ ፡ ሁሉ ፡
ያጠግባቸው ፡ ዘንድ ፡ ይሰበሰብላቸዋልን ?
፳፫ አለ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— በውኑ ፡
የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ አጭር ፡ ሆነ ? አሁን ፡
ቃሌ ፡ ይፈጸም ፡ ወይስ ፡ አይፈጸም ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ አንተ ፡ ታያለህ ፡ አለው ።
፳፬ ሙሴም ፡ ወጣ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ቃሎች ፡
ለሕዝቡ ፡ ነገረ ፤ ከሕዝቡ ፡ ሽማግሌዎችም ፡
ሰባውን ፡ ሰዎች ፡ ሰብስቦ ፡ በድንኳኑ ፡ ዙሪያ ፡
፳፭ አቆማቸው ። እግዚአብሔር ፡ በደመናው ፡
ወረደ ÷ ተናገረውም ÷ በእርሱም ፡ ላይ ፡ ከነበ

ረው ፡ መንፈስ ፡ ወስዶ ፡ በሰባው ፡ ሽማግሌዎች ፡
ላይ ፡ አደረገ ፤ መንፈሱም ፡ በላያቸው ፡ በደረ ፡
ጊዜ ፡ ትንቢት ፡ ተናገሩ ፤ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡
አልተናገሩም ።

፳፮ ከእነርሱም ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ በሰፈር ፡ ቀር
ተው ፡ ነበር ፥ የአንዱም ፡ ስም ፡ ኤልዳድ ፡ የሁ
ለተኛውም ፡ ሞዳድ ፡ ነበረ ፤ መንፈስም ፡ ወረ
ደባቸው ፤ እነርሱም ፡ ከተጻፉት ፡ ጋር ፡ ነበሩ ፡
ወደ ፡ ድንኳኑ ፡ ግን ፡ አልወጡም ፡ ነበር ፤ በሰ
ፈሩም ፡ ውስጥ ፡ ሳሉ ፡ ትንቢት ፡ ተናገሩ ።
፳፯ አንድ ፡ ጕበዝ ፡ ሰው ፡ እየሮጠ ፡ መጥቶ ፡— ኤል
ዳድና ፡ ሞዳድ ፡ በሰፈር ፡ ትንቢት ፡ ይናገራሉ ፡
፳፰ ብሎ ፡ ለሙሴ ፡ ነገረው ። ከልጅነቱ ፡ ጀምሮ ፡
የሙሴ ፡ አገልጋይ ፡ የነበረው ፡ የነዌ ፡ ልጅ ፡
ኢያሱ ፡— ጌታዬ ፡ ሙሴ ፡ ሆይ ፥ ከልክላቸው ፡
፳፱ አለው ። ሙሴም ፡— የእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡
ሁሉ ፡ ነቢያት ፡ ቢሆኑ ፥ እግዚአብሔርም ፡ በእ
ነርሱ ፡ ላይ ፡ መንፈሱን ፡ ቢያወርድ ፤ አንተ ፡
፴ ስለ ፡ እኔ ፡ ትቀናለህን ? አለው ። ሙሴም ፡
ከእስራኤል ፡ ሽማግሌዎች ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ሰፈር ፡
ተመለሰ ።

፴፩ ነፋስም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ፥
ከባሕርም ፡ ድርጭቶችን ፡ አመጣ ፥ የአንድ ፡
ቀንም ፡ መንገድ ፡ ያህል ፡ በዚህ ፥ የአንድ ፡
ቀንም ፡ መንገድ ፡ ያህል ፡ በዚያ ፡ በሰፈሩ ፡ ላይ ፡
በተናቸው ፤ በዚያም ፡ በሰፈሩ ፡ ዙሪያ ፡ ከፍታው ፡
ከምድር ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ።
፴፪ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሁሉ ፡ በሌሊትም ፡ ሁሉ ፡ በነ
ጋውም ፡ ሁሉ ፡ ሕዝቡ ፡ ተነሥተው ፡ ድርጭ
ትን ፡ ሰበሰቡ ፤ ከሁሉ ፡ ጥቂት ፡ የሰበሰበ ፡ አሥር ፡
የቆሮስ ፡ መስፈሪያ ፡ የሚያህል ፡ ሰበሰበ ፤ በሰ
፴፫ ፈሩም ፡ ዙሪያ ፡ ሁሉ ፡ አሰጡት ። ሥጋውም ፡
ገና ፡ በጥርሳቸው ፡ መካከል ፡ ሳለ ፡ ሳያኝኩትም ፥
የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ነደደ ፤
እግዚአብሔርም ፡ ሕዝቡን ፡ በታላቅ ፡ መቅሠ
፴፬ ፍት ፡ እጅግ ፡ መታ ። የጐመጁ ፡ ሕዝብ ፡ በዚያ ፡
ተቀብረዋልና ፡ የዚያ ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ የምኞት ፡
፴፭ መቃብር ፡ ተብሎ ፡ ተጠራ ። ሕዝቡም ፡ ከም
ኞት ፡ መቃብር ፡ ወደ ፡ ሐጼሮት ፡ ተጓዙ ፡ በሐ
ጼሮትም ፡ ተቀመጡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ ሙሴም ፡ ኢትዮጵያይቱን ፡ አግብቶአልና ፡
በገባት ፡ በኢትዮጵያይቱ ፡ ምክንያት ፡ ማርያ
፪ ምና ፡ አሮን ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ተናገሩ ። እነር
ሱም ፡— በውኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሙሴ ፡ ብቻ ፡
ተናግሮአልን ? በእኛስ ፡ ደግሞ ፡ የተናገረ ፡
አይደለምን ? አሉ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ሰማ ።
፫ ሙሴም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ካሉት ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
ይልቅ ፡ እጅግ ፡ ትሑት ፡ ሰው ፡ ነበረ ።

፬ እግዚአብሔርም ፡ ወዲያው ፡ ሙሴንና ፡ አሮ
ንን ፡ ማርያምንም ፡— ሦስታችሁ ፡ ወደ ፡ መገና
ኛው ፡ ድንኳን ፡ ውጡ ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ፤ ሦስ
፭ ቱም ፡ ወጡ ። እግዚአብሔርም ፡ በደመና ፡
ዓምድ ፡ ወረደ ፥ በድንኳኑም ፡ ደጃፍ ፡ ቆመ ፤
አሮንንና ፡ ማርያምን ፡ ጠራ ፥ ሁለቱም ፡ ወጡ ።
፮ እርሱም ፡— ቃሌን ፡ ስሙ ፤ በመካከላችሁ ፡
ነቢይ ፡ ቢኖር ፥ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ በራእይ ፡
እገለጥለታለሁ ፥ ወይም ፡ በሕልም ፡ እናገረዋ
፯ ለሁ ። ባሪያዬ ፡ ሙሴ ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አይደ
ለም ፤ እርሱ ፡ በቤቴ ፡ ሁሉ ፡ የታመነ ፡ ነው ።
፰ እኔ ፡ አፍ ፡ ለአፍ ፡ በግልጥ ፡ እናገረዋለሁ ፥ በም
ሳሌ ፡ አይደለም ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ መልክ ፡
ያያል ፤ በባሪያዬ ፡ በሙሴ ፡ ላይ ፡ ትናገሩ ፡ ዘንድ ፡
ስለ ፡ ምን ፡ አልፈራችሁም ? አለ ።

፱ እግዚአብሔርም ፡ ተቈጥቶባቸው ፡ ሄደ ።
፲ ደመናውም ፡ ከድንኳኑ ፡ ተነሣ ፤ እነሆም ፥ ማር
ያም ፡ ለምጻም ፡ ሆነች ፥ እንደ ፡ አመዳይም ፡
ነጭ ፡ ሆነች ፤ አሮንም ፡ ማርያምን ፡ ተመለ
ከተ ፥ እነሆም ፥ ለምጻም ፡ ሆና ፡ ነበር ። አሮ
፲፩ ንም ፡ ሙሴን ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ ስንፍና ፡ አድ
ርገናልና ፥ በድለንማልና ፡ እባክህ ፥ ኃጢአት ፡
አታድርግብን ። ከእናቱ ፡ ሆድ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡
፲፪ ግማሽ ፡ ሥጋው ፡ ተበልቶ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ እር
ስዋ ፡ አትሁን ። ሙሴም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
፲፫ እየጮኸ ፡— አቤቱ ፥ እባክህ ፥ አድናት ፡ አለው ።
፲፬ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— አባትዋ ፡ ምራ
ቁን ፡ በፊትዋ ፡ ቢተፋባት ፡ ስንኳ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡
ታፍር ፡ ዘንድ ፡ ይገባት ፡ ነበር ፤ ሰባት ፡ ቀን ፡
ከሰፈር ፡ ውጭ ፡ ተዘግታ ፡ ትቀመጥ ፥ ከዚያም ፡
፲፭ በኋላ ፡ ትመለስ ፡ አለው ። ማርያምም ፡ ከሰፈር ፡
ውጭ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ተዘግታ ፡ ተቀመጠች ፤
ማርያምም ፡ እስክትመለስ ፡ ድረስ ፡ ሕዝቡ ፡
አልተጓዙም ።

፲፮ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ሕዝቡ ፡ ከሐጼሮት ፡ ተጓዙ ፥
በፋራንም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሰፈሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪ ተናገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የምሰጣትን ፡
የከንዓንን ፡ ምድር ፡ ይሰልሉ ፡ ዘንድ ፡ ሰዎችን ፡
ላክ ፤ ከአባቶች ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ በመ
ካከላቸው ፡ አለቃ ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ትልካላ
፫ ችሁ ። ሙሴም ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡
ከፋራን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ላካቸው ፤ እነርሱም ፡
ሁሉ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ።
፬ ስማቸውም ፡ ይህ ፡ ነበረ ፤ ከሮቤል ፡ ነገድ ፡ የዘ
፭ ኩር ፡ ልጅ ፡ ሰሙኤል ፤ ከስምዖን ፡ ነገድ ፡ የሱሪ ፡
፮ ልጅ ፡ ሰፈጥ ፤ ከይሁዳ ፡ ነገድ ፡ የዮፎኒ ፡ ልጅ ፡
፯ ካሌብ ፤ ከይሳኮር ፡ ነገድ ፡ የዮሴፍ ፡ ልጅ ፡ ይግ
፰ አል ፤ ከኤፍሬም ፡ ነገድ ፡ የነዌ ፡ ልጅ ፡ አውሴ ፤
፱ ፲ ከብንያም ፡ ነገድ ፡ የራፉ ፡ ልጅ ፡ ፈልጢ ፤ ከዛብ
፲፩ ሎን ፡ ነገድ ፡ የሰዲ ፡ ልጅ ፡ ጉዲኤል ፤ ከዮሴፍ ፡
ነገድ ፡ እርሱም ፡ የምናሴ ፡ ነገድ ፡ የሱሲ ፡ ልጅ ፡
፲፪ ጋዲ ፤ ከዳን ፡ ነገድ ፡ የገማሊ ፡ ልጅ ፡ ዓሚኤል ፤
፲፫ ከአሴር ፡ ነገድ ፡ የሚካኤል ፡ ልጅ ፡ ሰቱር ፤
፲፬ ከንፍታሌም ፡ ነገድ ፡ የያቢ ፡ ልጅ ፡ ናቢ ፤
፲፭ ከጋድ ፡ ነገድ ፡ የማኪ ፡ ልጅ ፡ ጉዲኤል ።

፲፮ ምድሪቱን ፡ ይሰልሉ ፡ ዘንድ ፡ ሙሴ ፡ የላካቸው ፡ ሰዎች ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ። ሙሴም ፡ የነዌን ፡ ልጅ ፡ አውሴን ፡ ኢያሱ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።

፲፯ ሙሴም ፡ የከነዓንን ፡ ምድር ፡ ይሰልሉ ፡ ዘንድ ፡ ላካቸው ፥ አላቸውም ፡— ከዚህ ፡ በደቡብ ፡ ፲፰ በኩል ፡ ውጡ ፥ ወደ ፡ ተራሮችም ፡ ሂዱ ፤ ምድሪቱንም ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ሆነች ፥ በእርስዋም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ብርቱዎች ፡ ወይም ፡ ደካሞች ፥ ፲፱ ጥቂቶች ፡ ወይም ፡ ብዙዎች ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፥ የሚኖሩባትም ፡ ምድር ፡ መልካም ፡ ወይም ፡ ክፉ ፥ የሚኖሩባቸውም ፡ ከተሞች ፡ ሰፈሮች ፡ ወይም ፡ ፳ አምባች ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፥ ምድሪቱም ፡ ወፍራም ፡ ወይም ፡ ስስ ፥ ዛፍ ፡ ያለባት ፡ ወይም ፡ የሌለባት ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ እዩ ፤ ከምድሪቱ ፡ ፍሬ ፡ አምጡ ፤ አይዞአችሁ ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ወይኑ ፡ አስቀድሞ ፡ ፍሬ ፡ የሚያፈራበት ፡ ወራት ፡ ነበረ ።

፳፩ ወጡም ፡ ምድሪቱንም ፡ ከጺን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በሐማት ፡ ዳር ፡ እስካለችው ፡ እስከ ፡ ፳፪ ረአብ ፡ ድረስ ፡ ሰለሉ ። በደቡብም ፡ በኩል ፡ ወጡ ፥ ወደ ፡ ኬብሮንም ፡ ደረሱ ፤ በዚያም ፡ የዔናቅ ፡ ልጆች ፡ አኪመን ፥ ሴሲ ፥ ተላሚ ፡ ነበሩ ። ኬብሮንም ፡ በግብፅ ፡ ካለችው ፡ ከጣኔዎስ ፡ በፊት ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ተሠርታ ፡ ነበር ። ፳፫ ወደ ፡ ኤሽኮልም ፡ ሸለቆ ፡ መጡ ፥ ከዚያም ፡ ከወይኑ ፡ አንድ ፡ ዘለላ ፡ የነበረበትን ፡ አረግ ፡ ቈረጡ ፥ ሁለቱም ፡ ሰዎች ፡ በመሎጊያ ፡ ተሸከሙት ፤ ደግሞም ፡ ከሮማኑ ፡ ከበለሱም ፡ ፳፬ አመጡ ። የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከዚያ ፡ ስለ ፡ ቈረጡት ፡ ዘለላ ፡ የዚያን ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ የኤሽኮል ፡ ሸለቆ ፡ ብለው ፡ ጠሩት ።

፳፭ ምድሪቱንም ፡ ሰልለው ፡ ከአርባ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ፳፮ ተመለሱ ። በፋራን ፡ ምድረ ፡ በዳና ፡ በቃዴስ ፡ ወዳሉት ፡ ወደ ፡ ሙሴና ፡ ወደ ፡ አሮን ፡ ወደ ፡ እስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ሄደው ፡ ደረሱ ፤ ወሬውንም ፡ ለእነርሱና ፡ ለማኅበሩ ፡ ሁሉ ፡ ነገሩአቸው ፥ የምድሪቱንም ፡ ፍሬ ፡ አሳ ፳፯ ዩአቸው ። እንዲህም ፡ ብለው ፡ ነገሩት ፡— ወደ ፡ ላክኸን ፡ ምድር ፡ ደረስን ፥ እርስዋም ፡ ወተትና ፡ ማር ፡ ታፈስሳለች ፥ ፍሬዋም ፡ ይህ ፡ ነው ። ፳፰ ነገር ፡ ግን ፡ በምድሪቱ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ኃያላን ፡ ናቸው ፥ ከተሞቻቸውም ፡ የተመሸጉ ፡ እጅግም ፡ የጸኑ ፡ ናቸው ፤ ደግሞም ፡ በዚያ ፡ የዔናቅን ፡ ፳፱ ልጆች ፡ አየን ። በደቡብም ፡ ምድር ፡ አማሌቅ ፡ ተቀምጦአል ፤ በተራሮቹም ፡ ኬጢያዊና ፡ ኢያቡሳዊ ፡ አሞራዊም ፡ ተቀምጠዋል ፤ ከነዓናዊም ፡ በባሕር ፡ ዳርና ፡ በዮርዳኖስ ፡ አጠገብ ፡ ተቀምጦአል ።

፴ ካሌብም ፡ ሕዝቡን ፡ በሙሴ ፡ ፊት ፡ ዝም ፡ አሰኘና ፡— ማሸነፍ ፡ እንችላለንና ፡ እንውጣ ፥ ፴፩ እንውረሰው ፡ አለ ። ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የወጡ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡— በኃይል ፡ ከእኛ ፡ ይበረታሉና ፡ በዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ መውጣት ፡ አንችልም ፡ ፴፪ አሉ ። ስለ ፡ ሰለሉአትም ፡ ምድር ፡ ክፉ ፡ ወሬ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እያወሩ ፡— እኛ ፡ ዞረን ፡ የሰለልናት ፡ ምድር ፡ የሚኖሩባትን ፡ ሰዎች ፡ የምትበላ ፡ ምድር ፡ ናት ፤ በእርስዋም ፡ ዘንድ ፡ ያየናቸው ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ረጃጅም ፡ ሰዎች ፡ ፴፫ ናቸው ። በዚያም ፡ ከኔፊሊም ፡ ወገን ፡ የሆኑትን ፡ ኔፊሊም ፥ የዔናቅን ፡ ልጆች ፥ አየን ፤ እኛም ፡ በዓይናችን ፡ ግምት ፡ እንደ ፡ አንበጣዎች ፡ ነበርን ፥ ደግሞም ፡ እኛ ፡ በዓይናቸው ፡ ዘንድ ፡ እንዲሁ ፡ ነበርን ፡ አሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ ማኅበሩም ፡ ሁሉ ፡ድምፃቸውን ፡ አንሥተው ፡ ጮኹ ፤ ሕዝቡም ፡ በዚያ ፡ ሌሊት ፡ አለቀሱ ። ፪ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ በሙሴና ፡ በአሮን ፡ ላይ ፡ አጕረመረሙ ፤ ማኅበሩም ፡ ሁሉ ፡— በግብፅ ፡ ምድር ፡ ሳለን ፡ ምነው ፡ በሞትን ፡ ኖሮ ! ወይም ፡ በዚህ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ምነው ፡ በሞትን ፡ ፫ ኖሮ ! እግዚአብሔርም ፡ በሰይፍ ፡ እንሞት ፡ ዘንድ ፡ ወደዚች ፡ ምድር ፡ ለምን ፡ ያገባናል ? ሴቶቻችንና ፡ ልጆቻችን ፡ ምርኮ ፡ ይሆናሉ ፤ ወደ ፡ ግብፅ ፡ መመለስ ፡ አይሻለንምን ? አሉአቸው ።

፬ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡— ኑ ፥ አለቃ ፡ ሾመን ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ እንመለስ ፡ ተባባሉ ። ፭ ሙሴና ፡ አሮንም ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ጉባኤ ፡ ፊት ፡ በግምባራቸው ፡ ወደቁ ። ፮ ምድርን ፡ ከሰለሉት ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ የነዌ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱና ፡ የዮፎኒ ፡ ልጅ ፡ ካሌብ ፡ ልብሳቸውን ፡ ቀደዱ ፤ ፯ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡— ዞረን ፡ የሰለልናት ፡ ምድር ፡ እጅግ ፡ መልካም ፡ ናት ። ፰ እግዚአብሔርስ ፡ ከወደደን ፡ ወተትና ፡ ማር ፡ ወደምታፈስሰው ፡ ወደዚች ፡ ምድር ፡ ያገባናል ፡ እርስዋንም ፡ ይሰጠናል ። ፱ ነገር ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ አታምፁ ፤ እንደ ፡ እንጀራ ፡ ይሆኑልናልና ፡ የምድሪቱን ፡ ሰዎች ፡ አትፍሩ ፤ ጥላቸው ፡ ከላያቸው ፡ ተገፍፎአል ፥ እግዚአብሔርም ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ነው ፤ አትፍሩአቸው ፡ ብለው ፡ ተናገሩአቸው ። ፲ ማኅበሩ ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ በድንጋይ ፡ ይወግሩአቸው ፡ ዘንድ ፡ ተማከሩ ። የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ተገለጠ ።

፲፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— ይህ ፡ ሕዝብ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ይንቀኛል ? በፊቱስ ፡ በደረግሁት ፡ ተአምራት ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ አያምንብኝም ? ፲፪ ከርስታቸው ፡ አጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ በቸነፈር ፡ እመታቸዋለሁ ፤ አንተንም ፡ ከእነርሱ ፡ ለሚበዛና ፡ ለሚጠነክር ፡ ሕዝብ ፡ አደርግሃለሁ ፡ አለው ።

፲፫ ሙሴም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አለው ፡— ግብፃውያን ፡ ይሰማሉ ፤ ይህን ፡ ሕዝብ ፡ ከመካከላቸው ፡ በኃይልህ ፡ አውጥተኸዋልና ፤ ፲፬ ለዚችም ፡ ምድር ፡ ሰዎች ፡ ይናገራሉ ። አንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡ ሕዝብ ፡ መካከል ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ ሰምተዋል ፤ አንተም ፥ አቤቱ ፥ ፊት ፡ ለፊት ፡ ተገልጠሃል ፥ ደመናህም ፡ በላያቸው ፡

ቆሞአል ፥ በቀንም ፡ በደመና ፡ ዓምድ ፥ በሌ
ሊትም ፡ በእሳት ፡ ዓምድ ፡ በፊታቸው ፡ ትሄዳ
፲፭ ለህ ። ይህን ፡ ሕዝብ ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡
፲፮ ብትገድል ፡ ዝናህን ፡ የሰሙ ፡ አሕዛብ ፡— እግ
ዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ሕዝብ ፡ ወደ ፡ ማለላቸው ፡
ምድር ፡ ያገባቸው ፡ ዘንድ ፡ አልቻለምና ፡ በም
ድረ ፡ በዳ ፡ ገደላቸው ፡ ብለው ፡ ይናገራሉ ።
፲፯፲፰ አሁንም ፥ እባክህ ፡— እግዚአብሔር ፡ ታጋሽና ፡
ምሕረቱ ፡ የበዛ ፥ አበሳንና ፡ መተላለፍን ፡ ይቅር ፡
የሚል ፥ ኃጢአተኞችንም ፡ ከቶ ፡ የማያነጻ ፥
የአባቶችን ፡ ኃጢአት ፡ እስከ ፡ ሦስትና ፡ እስከ ፡
አራት ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ በልጆች ፡ ላይ ፡ የሚ
ያመጣ ፡ ነው ፡ ብለህ ፡ እንደ ፡ ተናገርህ ፥ የጌታ ፡
፲፱ ኃይል ፡ ታላቅ ፡ ይሁን ። ይህን ፡ ሕዝብ ፡ ከግ
ብፅ ፡ ምድር ፡ ከወጣህ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡
ድረስ ፡ ይቅር ፡ እንዳልሃቸው ፥ እባክህ ፥ እንደ ፡
ምሕረትህ ፡ ብዛት ፡ የዚህን ፡ ሕዝብ ፡ ኃጢአት ፡
ይቅር ፡ በል ።

፳ እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡— እንደ ፡ ቃልህ ፡
፳፩ ይቅር ፡ አልሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡
በእውነት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ ምድርን ፡
፳፪ ሁሉ ፡ ይሞላል ። በግብፅ ፡ ምድርና ፡ በምድረ ፡
በዳ ፡ ያደረግሁትን ፡ ተአምራቴንና ፡ ክብሬን ፡
ያዩ ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ አሥር ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡
፳፫ ተፈታተኑኝ ፥ ነገሬንም ፡ ስላልሰሙ ፥ በእው
ነት ፡ ለአባቶቻቸው ፡ የማልሁላቸውን ፡ ምድር ፡
አያዩም ፤ ከእነርሱም ፡ የናቀኝ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡
፳፬ አያያትም ፤ ባሪያዬ ፡ ካሌብ ፡ ግን ፡ ሌላ ፡ መን
ፈስ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ፈጽሞም ፡ ስለ ፡
ተከተለኝ ፡ እርሱ ፡ ወደ ፡ ገባበት ፡ ምድር ፡ አገ
፳፭ ባዋለሁ ፤ ዘሩም ፡ ይወርሳታል ። አማሌቅና ፡
ከነዓናዊውም ፡ በሸለቆው ፡ ውስጥ ፡ ተቀምጦ
አል ፤ በነጋው ፡ ተመልሳችሁ ፡ በኤርትራ ፡
ባሕር ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሂዱ ።

፳፮ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ እን
፳፯ ዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— የሚያጕረመርም
ብኝን ፡ ይህን ፡ ክፉ ፡ ሕዝብ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ እታ
ገሠዋለሁ ? በእኔ ፡ ላይ ፡ የሚያጕረመርሙትን ፡
የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ማጕረምረም ፡ ሰማሁ ።
፳፰ እንዲህ ፡ በላቸው ፡— እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡
በጆሮዬ ፡ እንደ ፡ ተናገራችሁት ፡ እንዲሁ ፡ በእ
ውነት ፡ አደርግባችኋለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብ
፳፱ ሔር ፤ በድኖቻችሁ ፡ በዚህ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ይወ
ድቃሉ ፤ የተቈጠራችሁ ፡ ሁሉ ፥ እንደ ፡ ቍጥ
ራችሁ ፡ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡
የሆነ ፡ ሁሉ ፥ እናንተ ፡ ያጕረመረማችሁብኝ ፥
፴ ከዮፎኒ ፡ ልጅ ፡ ከካሌብና ፡ ከነዌ ፡ ልጅ ፡ ከኢ
ያሱ ፡ በቀር ፡ በእርስዋ ፡ አስቀምጣችሁ ፡ ዘንድ ፡
እጄን ፡ ዘርግቼ ፡ ወደ ፡ ማልሁላችሁ ፡ ምድር ፡
፴፩ በእውነት ፡ እናንተ ፡ አትገቡም ። ምርኮኛ ፡
ይሆናሉ ፡ ያላችኋቸውን ፡ ልጆቻችሁን ፡ እነር
ሱን ፡ አገባቸዋለሁ ፥ እናንተም ፡ የናቃችኋትን ፡
፴፪ ምድር ፡ ያውቃሉ ። እናንተ ፡ ግን ፡ በድኖቻ
፴፫ ችሁ ፡ በዚህ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ይወድቃሉ ። ልጆ
ቻችሁም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ይቅ
በዘበዛሉ ፥ በድኖቻችሁም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡
እስኪጠፉ ፡ ድረስ ፡ ግልሙትናችሁን ፡ ይሸከ
፴፬ ማሉ ። ምድሪቱን ፡ በሰለላችሁበት ፡ ቀን ፡
ቍጥር ፥ አርባ ፡ ቀን ፥ ስለ ፡ አንድ ፡ ቀንም ፡
አንድ ፡ ዓመት ፥ ኃጢአታችሁን ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡
ትሸከማላችሁ ፥ ቍጣዬንም ፡ ታውቃላችሁ ።
፴፭ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡— በእኔ ፡ ላይ ፡ በተሰበ
ሰበ ፡ በዚህ ፡ ክፉ ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እን
ዲህ ፡ አደርጋለሁ ፡ ብዬ ፡ ተናገርሁ ፤ በዚህ ፡
ምድረ ፡ በዳ ፡ ያልቃሉ ፥ በዚያም ፡ ይሞታሉ ።

፴፮ ምድሪቱንም ፡ ሊሰልሉ ፡ ሙሴ ፡ ልኮአቸው ፡
የተመለሱት ፡ ሰዎች ፡ ክፉ ፡ ወሬም ፡ ስለ ፡ ምድ
ሪቱ ፡ እያወሩ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ማኅበሩ ፡ ሁሉ ፡
፴፯ እንዲያጕረመርሙ ፡ ያደረጉ ፥ ክፉ ፡ ወሬ ፡ ያወሩ ፡
እነዚያ ፡ ሰዎች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በመ
፴፰ ቅሠፍት ፡ ሞቱ ። ነገር ፡ ግን ፡ ምድሪቱን ፡ ሊሰ
ልሉ ፡ ከሄዱ ፡ ሰዎች ፡ የነዌ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱና ፡
የዮፎኒ ፡ ልጅ ፡ ካሌብ ፡ በሕይወት ፡ ተቀመጡ ።

፴፱ ሙሴም ፡ ይህን ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡
፵ ነገረ ፥ ሕዝቡም ፡ እጅግ ፡ አዘኑ ። በነጋውም ፡
ማልደው ፡ ተነሡ ፥ ወደ ፡ ተራራውም ፡ ራስ ፡
ወጥተው ፡— እነሆ ፥ መጣን ፤ እኛ ፡ በድለናልና ፡
እግዚአብሔር ፡ ወዳለው ፡ ስፍራ ፡ እንወጣለን ፡
፵፩ አሉ ። ሙሴም ፡ አለ ፡— የእግዚአብሔርን ፡
ትእዛዝ ፡ ለምን ፡ ትተላለፋላችሁ ? አይጠቅማ
፵፪ ችሁም ። እግዚአብሔር ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡
አይደለምና ፡ በጠላቶቻችሁ ፡ ፊት ፡ እንዳትወ
፵፫ ድቁ ፡ አትውጡ ። አማሌቃዊና ፡ ከነዓናዊ ፡ በፊ
ታችሁ ፡ ናቸውና ፡ በሰይፍ ፡ ትወድቃላችሁ ፤
እግዚአብሔርን ፡ ከመከተል ፡ ተመልሳችኋልና ፡
እግዚአብሔር ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ አይሆንም ።
፵፬ እነርሱ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ተራራው ፡ ራስ ፡ ሊወጡ ፡
ደፈሩ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡
ኪዳን ፡ ታቦትና ፡ ሙሴ ፡ ከሰፈሩ ፡ አልተነሡም ።
፵፭ በዚያም ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ የተቀመጡ ፡ አማሌቃ
ዊና ፡ ከነዓናዊ ፡ ወረዱ ፥ መትተዋቸውም ፡
እስከ ፡ ሔርማ ፡ ድረስ ፡ አሳደዱአቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪ ተናገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡
ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— ወደምሰጣችሁ ፡ ወደ ፡
፫ መኖሪያችሁ ፡ ምድር ፡ በገባችሁ ፡ ጊዜ ፥ ስእለ
ታችሁን ፡ ልትፈጽሙ ፥ ወይም ፡ በፈቃዳችሁ ፥
ወይም ፡ በበዓላችሁ ፥ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡
ሽታ ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ከበሬ ፡ ወይም ፡ ከበግ ፡
መንጋ ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ወይም ፡
መሥዋዕት ፡ የሚሆን ፡ የእሳት ፡ ቍርባን ፡ ለእ
፬ ፭ ግዚአብሔር ፡ ብታቀርቡ ፥ ቍርባኑን ፡ ለእግዚ
አብሔር ፡ የሚያቀርብ ፡ ከሚቃጠል ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ወይም ፡ ከሌላ ፡ መሥዋዕት ፡ ጋር ፡ ለእያ
ንዳንዱ ፡ ጠቦት ፡ የኢን ፡ መስፈሪያ ፡ አራተኛ ፡
እጅ ፡ በሆነ ፡ ዘይት ፡ የተለወሰ ፡ ከመስፈሪያው ፡

ከአሥር ፡ እጅ ፡ አንድ ፡ እጅ ፡ የሆነ ፡ መልካም ፡
ዱቄት ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፥ የኢን ፡ መስፈሪያ ፡
አራተኛ ፡ እጅ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ለመጠጥ ፡ ቍር
፮ ባን ፡ ያዘጋጃል ። ለአንዱም ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ የኢን ፡
መስፈሪያ ፡ ሢሶ ፡ በሆነ ፡ ዘይት ፡ የተለወሰ ፡
ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሁለት ፡ እጅ ፡
መልካም ፡ ዱቄት ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ ታዘጋ
ጃለህ ፤ የኢን ፡ መስፈሪያ ፡ ሢሶም ፡ የወይን ፡
፰ ጠጅ ፡ ለመጠጥ ፡ ቍርባን ፡ ታቀርባለህ ። ለሚ
ቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ ወይም ፡ ለሌላ ፡ መሥ
ዋዕት ፡ ወይም ፡ ስእለትን ፡ ለመፈጸም ፡ ወይም ፡
ለደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ ወይፈንን ፡ ለእግዚአ
፱ ብሔር ፡ ብታዘጋጅ ፥ ከወይፈኑ ፡ ጋር ፡ የኢን ፡
መስፈሪያ ፡ ግማሽ ፡ በሆነ ፡ ዘይት ፡ የተለወሰ ፡
ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሦስት ፡ እጅ ፡
መልካም ፡ ዱቄት ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ ታቀርብ
፲ ለህ ። ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲ
ሆን ፡ በእሳት ፡ ለተደረገ ፡ ቍርባን ፥ የኢን ፡
መስፈሪያ ፡ ግማሽ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ለመጠጥ ፡
ቍርባን ፡ ታቀርባለህ ።

፲፩ እንዲሁ ፡ ለእያንዳንዱ ፡ ወይፈን ፡ ወይም ፡
ለእያንዳንዱ ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ወይም ፡ ለእያንዳ
ንዱ ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ወይም ፡ የፍየል ፡ ጠቦት ፡
፲፪ ይደረጋል ። እንዳዘጋጃችሁት ፡ ቍጥር ፥ እን
ዲሁ ፡ እንደ ፡ ቍጥራቸው ፡ ለእያንዳንዱ ፡ ታደ
፲፫ ርጋላችሁ ። የአገር ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ ቍርባን ፡ በእ
ሳት ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፡ እንዲሁ ፡ ያደርጋል ።
፲፬ መጻተኛም ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ቢቀመጥ ፥ ወይም ፡
በትውልዳችሁ ፡ መካከል ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፥
ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡
ቍርባን ፡ በእሳት ፡ ቢያቀርብ ፥ እናንተ ፡ የም
ታደርጉትን ፡ እርሱ ፡ እንዲሁ ፡ ያደርጋል ።
፲፭ ለእናንተ ፡ በጉባኤው ፡ ላላችሁ ፡ በእናንተም ፡
መካከል ፡ ለሚቀመጥ ፡ መጻተኛ ፡ አንድ ፡ ሥር
ዓት ፡ ይሆናል ፥ ለልጅ ፡ ልጃችሁም ፡ የዘላለም ፡
ሥርዓት ፡ ይሆናል ፤ እናንተ ፡ እንደ ፡ ሆናችሁ ፡
እንዲሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ መጻተኛ ፡
፲፮ ይሆናል ። ለእናንተና ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ለሚ
ቀመጥ ፡ መጻተኛ ፡ አንድ ፡ ሕግና ፡ አንድ ፡
ፍርድ ፡ ይሆናል ።

፲፯ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፲፰ ተናገረው ፦— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡
ብለህ ፡ ንገራቸው ፦— ወደማመጣችሁ ፡ ምድር ፡
፲፱ በገባችሁ ፡ ጊዜ ፥ እናንተ ፡ የምድሪቱን ፡ እን
ጀራ ፡ በበላችሁ ፡ ጊዜ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የማ
፳ ንሣት ፡ ቍርባን ፡ ታደርጋላችሁ ። መጀመሪያ ፡
ከምታደርጉት ፡ ሊጥ ፡ አንድ ፡ እንጐቻ ፡ ለማን
ሣት ፡ ቍርባን ፡ ታቀርባላችሁ ፤ ከአውድማም ፡
እንደምታነሡት ፡ ቍርባን ፡ እንዲሁ ፡ ታነሣላ
፳፩ ችሁ ። መጀመሪያም ፡ ከምታደርጉት ፡ ሊጥ ፡
የማንሣት ፡ ቍርባን ፡ እስከ ፡ ልጅ ፡ ልጃችሁ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ትሰጣላችሁ ።

፳፪ ብትስቱም ፥ እግዚአብሔርም ፡ ለሙሴ ፡ ያዘ
ዛቸውን ፡ እነዚህን ፡ ትእዛዛት ፡ ሁሉ ፡ ባታደ
፳፫ ርጉ ፥ እግዚአብሔር ፡ ካዘዘበት ፡ ከፊተኛው ፡
ቀን ፡ ጀምሮ ፡ ወደ ፡ ፊትም ፡ እስከ ፡ ልጅ ፡ ልጃ
ችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ ያዘዛች
፳፬ ሁን ፡ ሁሉ ፡ ባታደርጉ ፥ ማኅበሩ ፡ ሳያውቁ ፡
በስሕተት ፡ ቢደረግ ፥ ማኅበሩ ፡ ሁሉ ፡ ለሚቃ
ጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ከእህሉ ፡ ቍርባንና ፡ ከመ
ጠጡ ፡ ቍርባን ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ ለእግዚአ
ብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ አንድ ፡ ወይ
ፈን ፥ ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡
፳፭ ፍየል ፡ ያቀርባሉ ። ካህኑም ፡ ለእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ያስተሰርይላቸዋል ፥
ስሕተትም ፡ ነበረና ፡ ይሰረይላቸዋል ፤ ስለ ፡ ስሕ
ተታቸውም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቍርባናቸውን ፡
በእሳት ፡ አቀርበዋል ፥ ለእግዚአብሔርም ፡ የኃ
፳፮ ጢአታቸውን ፡ መሥዋዕት ፡ አቀርበዋል ። በሕ
ዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ ያለ ፡ እውቀት ፡ ተደርጎ
አልና ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡
በመካከላቸውም ፡ ለሚኖሩት ፡ መጻተኞች ፡ ስር
የት ፡ ይደረግላቸዋል ።

፳፯ አንድ ፡ ሰው ፡ ሳያውቅ ፡ ኃጢአት ፡ ቢሠራ ፥
ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ አንዲት ፡ የአንድ ፡
፳፰ ዓመት ፡ እንስት ፡ ፍየል ፡ ያቀርባል ። ኃጢአት ፡
ሠርቶ ፡ ሳያውቅ ፥ ለሳተ ፡ ለዚያ ፡ ሰው ፡ ካህኑ ፡
ያስተሰርይለታል ፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያስ
፳፱ ተሰርይለታል ፥ ይሰረይለትማል ። ትውልዱ ፡
በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከልም ፡ ቢሆን ፥
ወይም ፡ በመካከላቸው ፡ የሚቀመጥ ፡ መጻተኛ ፡
ቢሆን ፥ ሳያውቅ ፡ ኃጢአትን ፡ ለሚሠራ ፡
፴ ሁሉ ፡ ሕጉ ፡ አንድ ፡ ይሆንለታል ። የአገር ፡
ልጅ ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ መጻተኛ ፡ ቢሆን ፥ አን
ዳች ፡ በትዕቢት ፡ የሚያደርግ ፡ ሰው ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ ሰድቦአል ፤ ያም ፡ ሰው ፡ ከሕዝቡ ፡
፴፩ መካከል ፡ ተለይቶ ፡ ይጠፋል ። የእግዚአብሔ
ርን ፡ ቃል ፡ ስለ ፡ ናቀ ፥ ትእዛዙንም ፡ ስለ ፡ ሰበረ ፥
ያ ፡ ሰው ፡ ፈጽሞ ፡ ይጥፋ ፤ ኃጢአቱ ፡ በራሱ ፡
ላይ ፡ ነው ።

፴፪ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ሳሉ ፡
አንድ ፡ ሰው ፡ በሰንበት ፡ ቀን ፡ እንጨት ፡ ሲለ
፴፫ ቅም ፡ አገኙ ። እንጨትም ፡ ሲለቅም ፡ ያገኙት ፡
ሰዎች ፡ ወደ ፡ ሙሴና ፡ ወደ ፡ አሮን ፡ ወደ ፡ ማኅ
፴፬ በሩም ፡ ሁሉ ፡ አመጡት ። ያደርጉበትም ፡
ዘንድ ፡ የሚገባው ፡ አልተገለጠምና ፡ በግዞት ፡
፴፭ አስቀመጡት ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፦—
ሰውዮው ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደል ፤ ከሰፈሩ ፡ ውጭ ፡
ማኅበሩ ፡ ሁሉ ፡ በድንጋይ ፡ ይውገሩት ፡ አለው ።
፴፮ ማኅበሩም ፡ ሁሉ ፡ ከሰፈሩ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አወ
ጡት ፥ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡
እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ በድንጋይ ፡ ወገሩት ።

፴፯ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፴፰ ተናገረው ፦— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡
በላቸው ፦— እነርሱም ፡ ትውልዶቻቸውም ፡
በልብሳቸው ፡ ጫፍ ፡ ዘርፍ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፥

በዘርፉም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሰማያዊ ፡ ፈትል ፡ ያደ
፴፱፤ ርጉ ፡ ዘንድ ፡ እዘዛቸው ። የእግዚአብሔርንም ፡
ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ታስቡና ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፥
እርስዋን ፡ በመከተል ፡ ያመነዘራችሁባትን ፡ የል
ባችሁንና ፡ የዓይኖቻችሁን ፡ ፈቃድ ፡ እንዳት
፵፤ ከተሉ ፥ ትእዛዜን ፡ ሁሉ ፡ ታስቡና ፡ ታደርጉ ፡
ዘንድ ፥ ለአምላካችሁም ፡ ቅዱሳን ፡ ትሆኑ ፡
ዘንድ ፡ ዘርፉ ፡ በልብሳችሁ ፡ ላይ ፡ እንዲታይ ፡
፵፩፤ ይሁን ። እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡
ነኝ ፤ አምላክ ፡ እሆናችሁ ፡ ዘንድ ፡ ከግብፅ ፡
ምድር ፡ ያወጣኋችሁ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡
አምላካችሁ ፡ ነኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩፤ የሌዊም ፡ ልጅ ፡ የቀዓት ፡ ልጅ ፡ የይስዓር ፡ ልጅ ፡
ቆሬ ፡ ከሮቤልም ፡ ልጆች ፡ የኤልያብ ፡ ልጆች ፡
ዳታንና ፡ አቤሮን ፡ የፋሌትም ፡ ልጅ ፡ ኦን ፡
፪፤ በሙሴ ፡ ላይ ፡ ተነሡ ። ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ሰዎች ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡
ወሰዱ ፤ ከጉባኤው ፡ የተመረጡ ፡ ዝናቸውም ፡
፫፤ የተሰማ ፡ የማኅበሩ ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ። በሙ
ሴና ፡ በአሮን ፡ ላይ ፡ ተሰብስበው ፡— ማኅበሩ ፡
ሁሉ ፡ እያንዳንዳቸው ፡ ቅዱሳን ፡ ናቸውና ፥
እግዚአብሔርም ፡ በመካከላቸው ፡ ነውና ፡ እና
ንተ ፡ እጅግ ፡ አብዝታችኋል ፤ በእግዚአብሔ
ርም ፡ ጉባኤ ፡ ላይ ፡ ለምን ፡ ትታበያላችሁ ?
አሉ ።

፬፤ ሙሴም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ በግምባሩ ፡ ወደቀ ፤
፭፤ ለቆሬም ፡ ለወገኑም ፡ ሁሉ ፡— ነገ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ለእርሱ ፡ የሚሆነውን ፥ ቅዱስም ፡
የሚሆነውን ፡ ያስታውቃል ፤ የመረጠውንም ፡
፮፤ ሰው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ያቀርበዋል ። እንዲሁ ፡
አድርጉ ፤ ቆሬና ፡ ወገንህ ፡ ሁሉ ፥ ጥናዎቹን ፡
፯፤ ውሰዱ ፤ ነገም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እሳት ፡
አድርጉባቸው ፥ ዕጣንም ፡ ጨምሩባቸው ፤ እን
ዲህም ፡ ይሆናል ፤ እግዚአብሔር ፡ የሚመር
ጠው ፡ እርሱ ፡ ቅዱስ ፡ ይሆናል ፤ እናንተ ፡
የሌዊ ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ እጅግ ፡ አብዝታችኋል ፡
፰፤ ብሎ ፡ ተናገራቸው ። ሙሴም ፡ ቆሬን ፡ አለው ፡—
፱፤ እናንተ ፡ የሌዊ ፡ ልጆች ፥ ስሙ ፤ የእስራኤል ፡
አምላክ ፡ ከእስራኤል ፡ ማኅበር ፡ የለያችሁ ፥
የእግዚአብሔርንም ፡ ማደሪያ ፡ አገልግሎት ፡
ትሠሩ ፡ ዘንድ ፥ እንድታገለግሉአቸውም ፡ በማ
ኅበሩ ፡ ፊት ፡ ትቆሙ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡
፲፤ ያቀረባችሁ ፡ አይበቃችሁምን ? አንተን ፡ ከአ
ንተም ፡ ጋር ፡ የሌዊን ፡ ልጆች ፡ ወንድሞች
ህን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አቅርቦአል ፤ ክህነት
፲፩፤ ንም ፡ ደግሞ ፡ ትፈልጋላችሁን ? ስለዚህም ፡
አንተና ፡ ወገንህ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡
ተሰብስባችኋል ፤ በእርሱም ፡ ላይ ፡ ታጕረመ
ርሙ ፡ ዘንድ ፡ አሮን ፡ ማን ፡ ነው ?

፲፪፤ ሙሴም ፡ የኤልያብን ፡ ልጆች ፡ ዳታንና ፡ አቤ
ሮንን ፡ እንዲጠሩአቸው ፡ ላከ ፤ እነርሱም ፡—
፲፫፤ አንመጣም ፤ በምድረ ፡ በዳ ፡ ትገድለን ፡ ዘንድ ፡
ወተትና ፡ ማር ፡ ከምታፈስሰው ፡ ምድር ፡ ያወ
ጣኸን ፡ አይበቃህምን ? ደግመህ ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡
ራስህን ፡ አለቃ ፡ ታደርጋለህን ? ደግሞ ፡ ወተ ፲፬፤
ትና ፡ ማር ፡ ወደምታፈስስ ፡ ምድር ፡ አላገባ
ኸንም ፥ እርሻና ፡ ወይንም ፡ አላወረስኸንም ፤
የእነዚህንስ ፡ ሰዎች ፡ ዓይኖቻቸውን ፡ ታወጣለ
ህን ? አንመጣም ፡ አሉ ።

ሙሴም ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ፥ እግዚአብሔር ፲፭፤
ንም ፡— ወደ ፡ ቍርባናቸው ፡ አትመልከት ፤
እኔ ፡ ከእነርሱ ፡ አንድ ፡ አህያ ፡ ስንኳ ፡ አልወሰ
ድሁም ፥ ከእነርሱም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ አልበደል
ሁም ፡ አለው ። ሙሴም ፡ ቆሬን ፡— ነገ ፡ አንተ ፥ ፲፮፤
ወገንህም ፡ ሁሉ ፥ አሮንም ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ሁኑ ፤ ሁላችሁም ፡ ጥናዎቻችሁን ፡ ፲፯፤
ውሰዱ ፥ ዕጣንም ፡ አድርጉባቸው ፥ እያንዳንዳ
ችሁም ፡ ጥናዎቻችሁን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር
ፊት ፡ አምጡ ፥ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ጥናዎች ፤
አንተ ፡ ደግሞ ፡ አሮንም ፡ ጥናዎቻችሁን ፡
አምጡ ፡ አለው ። እያንዳንዱም ፡ ጥናውን ፡ ፲፰፤
ወሰደ ፥ እሳትም ፡ አደረገበት ፥ ዕጣንም ፡ ጨመ
ረበት ፥ ከሙሴና ፡ ከአሮንም ፡ ጋር ፡ በመገና
ኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ቆመ ። ቆሬም ፡ ማኅበ ፲፱፤
ሩን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡
በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ሰበሰበ ፤ የእግዚአብሔርም ፡
ክብር ፡ ለማኅበሩ ፡ ሁሉ ፡ ተገለጠ ።

እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ እን ፳፤
ዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— ሁሉን ፡ በቅጽበት ፡ ፳፩፤
አጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ ከዚህ ፡ ማኅበር ፡ መካከል ፡
ፈቀቅ ፡ በሉ ። እነርሱም ፡ በግምባራቸው ፡ ወድ ፳፪፤
ቀው ፡— አምላክ ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ የሰው ፡ ሁሉ ፡
ነፍስ ፡ አምላክ ፥ አንድ ፡ ሰው ፡ ኃጢአት ፡
ቢሠራ ፡ አንተ ፡ በማኅበሩ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ትቈ
ጣለህን ? አሉ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ ፳፫፤
እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ለማኅበሩ ፡— ፳፬፤
ከቆሬና ፡ ከዳታን ፡ ከአቤሮንም ፡ ማደሪያ ፡ ዙሪያ ፡
ፈቀቅ ፡ በሉ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ።

ሙሴም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ዳታንና ፡ ወደ ፡ ፳፭፤
አቤሮን ፡ ሄደ ፤ የእስራኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡
ተከተሉት ። ማኅበሩንም ፡— እባካችሁ ፥ ከእነ ፳፮፤
ዚህ ፡ ክፉዎች ፡ ድንኳን ፡ ፈቀቅ ፡ በሉ ፤ በኃጢ
አታቸውም ፡ ሁሉ ፡ እንዳትጠፉ ፡ ለእነርሱ ፡
የሆነውን ፡ ሁሉ ፡ አትንኩ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ።
ከቆሬና ፡ ከዳታን ፡ ከአቤሮንም ፡ ማደሪያ ፡ ከዙ ፳፯፤
ሪያውም ፡ ሁሉ ፡ ፈቀቅ ፡ አሉ ፤ ዳታንና ፡ አቤ
ሮንም ፡ ሴቶቻቸውም ፡ ልጆቻቸውም ፡ ሕፃናቶ
ቻቸውም ፡ ወጥተው ፡ በድንኳኖቻቸው ፡ ደጃፍ ፡
ቆሙ ። ሙሴም ፡ አለ ፡— ይህን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ፳፰፤
አደርግ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ላከኝ ፡
እንጂ ፡ ከልቤ ፡ እንዳይደለ ፡ በዚህ ፡ ታውቃላ
ችሁ ። እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ሰው ፡ እንደሚሞት ፡ ፳፱፤
ቢሞቱ ፥ ወይም ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ቢቀሠፉ ፡
እግዚአብሔር ፡ አልላከኝም ። እግዚአብሔር ፡ ፴፤
ግን ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ ቢፈጥር ፥ ምድርም ፡ አፍዋን ፡
ከፍታ ፡ እነርሱን ፡ ለእነርሱም ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡

ብትውጣቸው ፥ በሕይወታቸውም ፡ ወደ ፡
ሲኦል ፡ ቢወርዱ ፥ ያን ፡ ጊዜ ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡
እግዚአብሔርን ፡ እንደ ፡ ናቁ ፡ ታውቃላችሁ ።
፴፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ይህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ መናገር ፡
ባፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ ከበታቻቸው ፡ ያለው ፡ መሬት ፡
፴፪ ተሰነጠቀ ፤ ምድሪቱም ፡ አፍዋን ፡ ከፍታ ፡ እነ
ርሱን ፡ ቤተ ፡ ሰቦቻቸውንም ፥ ለቆሬም ፡ የነ
በሩትን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፥ ዕቃዎቻቸውንም ፡
፴፫ ሁሉ ፡ ዋጠቻቸው ። እነርሱም ፡ ለእነርሱም ፡
የነበሩ ፡ ሁሉ ፡ በሕይወታቸው ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡
ወረዱ ፤ ምድሪቱም ፡ ተዘጋችባቸው ፥ ከጉባኤ
፴፬ ውም ፡ መከከል ፡ ጠፉ ። በዙሪያቸው ፡ የነበሩ ፡
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ከጩኸታቸው ፡
የተነሣ ፡— ምድሪቱ ፡ እንዳትውጠን ፡ ብለው ፡
፴፭ በረሩ ። እሳትም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
ወጥታ ፡ ያጥኑ ፡ የነበሩትን ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡
አምሳ ፡ ሰዎች ፡ በላች ።
፴፮ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፴፯ ተናገረው ፡— ለካህኑ ፡ ለአሮን ፡ ልጅ ፡ ለአልዓዛር ፡
እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገረው ፡— ተቀድሰዋልና ፡ ጥና
ዎቹን ፡ ከተቃጠሉት ፡ ዘንድ ፡ ውሰድ ፥ እሳቱ
፴፰ ንም ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ጣለው ፤ በኃጢአታቸው ፡
ሰውነታቸውን ፡ ያጠፉትን ፡ የእነዚያን ፡ ሰዎች ፡
ጥናዎች ፡ ጠፍጥፈህ ፡ ለመሠዊያ ፡ መለበጫ ፡
አድርጋቸው ፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አቅርበ
ዋቸዋልና ፡ የተቀደሱ ፡ ናቸው ፥ ለእስራኤልም ፡
፴፱ ልጆች ፡ ምልክት ፡ ይሆናሉ ። ካህኑም ፡ አልዓ
ዛር ፡ የተቃጠሉት ፡ ሰዎች ፡ ያቀረቡአቸውን ፡
የናስ ፡ ጥናዎች ፡ ወስዶ ፡ ጠፍጥፎም ፡ ለመሠዊ
፵ ያው ፡ መለበጫ ፡ አደረጋቸው ። በቆሬና ፡ በወ
ገኑ ፡ የደረሰው ፡ እንዳይደርስበት ፥ ከአሮን ፡
ልጆች ፡ ያልሆነ ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ዕጣን ፡ ያጥን ፡ ዘንድ ፡ እንዳይቀርብ ፥ እግ
ዚአብሔር ፡ በሙሴ ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፥ ለእስ
ራኤል ፡ ልጆች ፡ መታሰቢያ ፡ አደረጋቸው ።
፵፩ በነጋውም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡
ሁሉ ፡— እናንተ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕዝብ ፡
ገድላችኋል ፡ ብለው ፡ በሙሴና ፡ በአሮን ፡ ላይ ፡
፵፪ አጕረመረሙ ። እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ማኅበሩ ፡
በሙሴና ፡ በአሮን ፡ ላይ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡
ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ አዩ ፤ እነሆም ፥
ደመናው ፡ ሸፈነው ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡
፵፫ ተገለጠ ። ሙሴና ፡ አሮንም ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡
፵፬ ድንኳን ፡ ፊት ፡ መጡ ። እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡
፵፭ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ከዚህ ፡ ማኅበር ፡
መከከል ፡ ፈቀቅ ፡ በሉ ፥ እኔም ፡ በቅጽበት ፡
አጠፋቸዋለሁ ። በግምባራቸውም ፡ ወደቁ ።
፵፮ ሙሴም ፡ አሮንን ፡— ጥናህን ፡ ውሰድ ፥ ከመሠ
ዊያውም ፡ ላይ ፡ እሳት ፡ አድርግበት ፥ ዕጣንም ፡
ጨምርበት ፥ ወደ ፡ ማኅበሩም ፡ ፈጥነህ ፡ ውሰ
ደው ፡ አስተስርይላቸውም ፤ ከእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ቍጣ ፡ ወጥቶአልና ፡ መቅሠፍት ፡ ጀምሮ
፵፯ አል ፡ አለው ። አሮንም ፡ ሙሴ ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡
ጥናውን ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ ጉባኤው ፡ መከከል ፡
ሮጠ ፤ እነሆም ፥ መቅሠፍቱ ፡ በሕዝቡ ፡ መከ
ከል ፡ ጀምሮ ፡ ነበር ፤ ዕጣንም ፡ ጨመረ ፥ ለሕ
፵፰ ዝቡም ፡ አስተሰረየላቸው ። በሙታንና ፡ በሕ
ያዋን ፡ መከከል ፡ ቆመ ፤ መቅሠፍቱም ፡ ተከለ
፵፱ ከለ ። በቆሬም ፡ ምክንያት ፡ ከሞቱት ፡ ሌላ ፡
በመቅሠፍቱ ፡ የሞቱት ፡ አሥራ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡
፶ ሰባት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። አሮንም ፡ ወደ ፡ ሙሴ ፡
ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ተመለሰ ፤
መቅሠፍቱም ፡ ተከለከለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪ ተናገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ንገራቸው ፥
ከእነርሱም ፡ ከእያንዳንዱ ፡ ከየአባቶቻቸው ፡
ቤት ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ በትር ፥ ከአለቆቻቸው ፡
ከየአባቶቻቸው ፡ ቤት ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ በት
ሮች ፥ ውሰድ ፤ የእያንዳንዱንም ፡ ስም ፡ በየበ
፫ ትሩ ፡ ላይ ፡ ጻፍ ። አንድ ፡ በትርም ፡ ለአባቶቻ
ቸው ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ ይሆናልና ፡ በሌዊ ፡ በትር ፡
፬ ላይ ፡ የአሮንን ፡ ስም ፡ ጻፍ ። እኔ ፡ ከእናንተ ፡
ጋር ፡ በምገናኝበት ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡
፭ ውስጥ ፡ በምስክሩ ፡ ፊት ፡ አኑራቸው ። እንዲ
ህም ፡ ይሆናል ፤ የመረጥሁት ፡ ሰው ፡ በትር ፡
ታቈጠቍጣለች ፤ በእናንተም ፡ ላይ ፡ የሚያጕረ
መርሙብችሁን ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ማጕ
፮ ረምረም ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ አጠፋለሁ ። ሙሴም ፡
ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተናገራቸው ፤ አለቆቻ
ቸው ፡ ሁሉ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ በትሮች ፥ እያ
ንዳንዱም ፡ አለቃ ፡ በየአባቱ ፡ ቤት ፡ አንድ ፡
አንድ ፡ በትር ፥ ሰጡት ፤ የአሮንም ፡ በትር ፡
፯ በበትሮቻቸው ፡ መከከል ፡ ነበረች ። ሙሴም ፡
በትሮቹን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በምስክሩ ፡
ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ አኖራቸው ።
፰ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በነጋው ፡ ሙሴ ፡ ወደ ፡ ምስ
ክሩ ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ገባ ፤ እነሆም ፥ ለሌዊ ፡
ቤት ፡ የሆነች ፡ የአሮን ፡ በትር ፡ አቈጠቈጠች ፥
ለመለመችም ፥ አበባም ፡ አወጣች ፥ የበሰለ ፡
፱ ለውዝም ፡ አፈራች ። ሙሴም ፡ በትሮችን ፡
ሁሉ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡
ልጆች ፡ ሁሉ ፡ አወጣቸው ፤ እነርሱም ፡ አዩ ፥ እያ
፲ ንዳንዱም ፡ በትሩን ፡ ወሰደ ። እግዚአብሔርም ፡
ሙሴን ፡— የአሮንን ፡ በትር ፡ ወደ ፡ ምስክሩ ፡
ፊት ፡ መልስ ፤ ማጕረምረማቸው ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡
እንዲጠፋ ፡ እነርሱም ፡ እንዳይሞቱ ፡ ለሚያምፁ
ብኝ ፡ ልጆች ፡ ምልክት ፡ ሆና ፡ ትጠበቅ ፡ አለው ።
፲፩ ሙሴም ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ፤ እግዚአብሔር ፡
እንዳዘዘው ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ።
፲፪ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሙሴን ፡— እነሆ ፥
እንሞታለን ፥ እንጠፋለን ፥ ሁላችንም ፡ እንጠ
፲፫ ፋለን ። የሚቀርብ ፡ ሁሉ ፥ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ማደሪያ ፡ የሚቀርብ ፥ ይሞታል ፤ በውኑ ፡
ሁላችን ፡ እንሞታለንን ? ብለው ፡ ተናገሩት ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ አሮንን ፡ አለው ፡— አንተ ፡ ከአንተም ፡ ጋር ፡ ልጆችህና ፡ የአባቶችህ ፡ ቤት ፡ የመቅደስን ፡ ኃጢአት ፡ ትሸከማላችሁ ፤ አንተም ፡ ከአንተም ፡ ጋር ፡ ልጆችህ ፡ የክህነታችሁን ፡ ኃጢአት ፡ ትሸከማላችሁ ። ፪ ደግሞም ፡ የአባትህን ፡ የሌዊን ፡ ነገድ ፡ ወንድሞችህን ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አቅርብ ፤ ከአንተም ፡ ጋር ፡ በአንድነት ፡ ይሁኑ ፥ ያገልግሉህም ፤ አንተ ፡ ግን ፡ ከአንተም ፡ ጋር ፡ ልጆችህ ፡ በምስክሩ ፡ ድንኳን ፡ ፊት ፡ ትሆናላችሁ ። ፫ እነርሱም ፡ ትእዛዝህን ፡ የድንኳኑንም ፡ ሁሉ ፡ አገልግሎት ፡ ይጠብቁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እንዳይሞቱ ፥ እናንተም ፡ ደግሞ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ እንዳትሞቱ ፥ እነርሱ ፡ ወደ ፡ መቅደሱ ፡ ዕቃና ፡ ወደ ፡ መሠዊያው ፡ አይቅረቡ ። ፬ ነገር ፡ ግን ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ በአንድነት ፡ ይሁኑ ፥ ለድንኳኑም ፡ አገልግሎት ፡ ሁሉ ፡ የመገናኛውን ፡ ድንኳን ፡ ይጠብቁ ፤ ሌላም ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ አይቅረብ ። ፭ እንደ ፡ ገና ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ቍጣ ፡ እንዳይሆንባቸው ፡ እናንተ ፡ መቅደሱንና ፡ መሠዊያውን ፡ ጠብቁ ። ፮ እኔም ፥ እነሆ ፥ ሌዋውያንን ፡ ወንድሞቻችሁን ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ወስጀአለሁ ፤ የመገናኛውን ፡ ድንኳን ፡ አገልግሎት ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተሰጡ ፡ ለእናንተ ፡ ስጦታ ፡ ናቸው ። ፯ አንተም ፡ ከአንተም ፡ ጋር ፡ ልጆችህ ፡ ለመሠዊያው ፡ ሥራ ፡ የሚሆነውን ፡ ሁሉ ፥ በመጋረጃውም ፡ ውስጥ ፡ የሚሆነውን ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ክህነታችሁን ፡ ጠብቁ ፥ አገልግሉም ፤ ክህነቱን ፡ ለስጦታ ፡ አገልግሎት ፡ ሰጥቼአችኋለሁ ፤ ሌላም ፡ ሰው ፡ ቢቀርብ ፡ ይገደል ።

፰ እግዚአብሔርም ፡ አሮንን ፡ ተናገረው ፡ እንዲህም ፡ አለው ፡— እነሆ ፥ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ለእኔ ፡ የቀደሱትን ፡ የማንሣት ፡ ቍርባኔን ፡ ሁሉ ፡ ለአንተ ፡ ሰጥቼሃለሁ ፤ ስለ ፡ መቀባትህ ፡ ለአንተና ፡ ለልጆችህ ፡ ድርሻ ፡ እንዲሆን ፡ ለዘላለም ፡ ሰጥቼሃለሁ ። ፱ በእሳት ፡ ከሚቀርበው ፡ ከተቀደሰው ፡ ይህ ፡ ለአንተ ፡ ይሆናል ፤ ለእኔ ፡ የሚያመጡት ፡ መባቸው ፡ ሁሉ ፥ የእህሉ ፡ ቍርባናቸው ፡ ሁሉ ፥ የኃጢአታቸውም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁሉ ፥ የበደላቸውም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁሉ ፥ ለአንተ ፡ ለልጆችህም ፡ የተቀደሰ ፡ ይሆናል ። ፲ በተቀደሰ ፡ ስፍራ ፡ ብላው ፤ ወንዶች ፡ ሁሉ ፡ ይብሉት ፤ የተቀደሰ ፡ ይሆንልሃል ። ፲፩ ይህም ፡ ለአንተ ፡ ነው ፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ለስጦታ ፡ ያቀረቡትን ፡ የማንሣትና ፡ የመወዝወዝ ፡ ቍርባን ፡ ሁሉ ፡ ለአንተ ፡ ከአንተም ፡ ጋር ፡ ለወንዶችና ፡ ለሴቶች ፡ ልጆችህ ፡ ድርሻ ፡ እንዲሆን ፡ ለዘላለም ፡ ሰጥቼሃለሁ ፤ በቤትህ ፡ ውስጥ ፡ ንጹሕ ፡ የሆነ ፡ ሁሉ ፡ ይብላው ። ፲፪ ለእግዚአብሔር ፡ ከሚሰጡት ፡ የፍሬ ፡ መጀመሪያ ፡ ከዘይትና ፡ ከወይን ፡ ከእህልም ፡ የተመረጠውን ፡ ሁሉ ፡ ለአንተ ፡ ሰጥቼሃለሁ ። ፲፫ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚያመጡት ፡ በምድራቸው ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ የፍሬ ፡ መጀመሪያ ፡ ለአንተ ፡ ይሆናል ፤ በቤትህ ፡ ውስጥ ፡ ንጹሕ ፡ የሆነ ፡ ሁሉ ፡ ይብላው ። ፲፬ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ እርም ፡ የሆነው ፡ ሁሉ ፡ ለአንተ ፡ ይሆናል ። ፲፭ ከሰው ፡ ወይም ፡ ከእንስሳ ፡ ቢሆን ፥ ለእግዚአብሔር ፡ ከሚያቀርቡት ፡ ሥጋ ፡ ሁሉ ፡ ማኅፀን ፡ የሚከፍት ፡ ሁሉ ፡ ለአንተ ፡ ይሆናል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የሰውን ፡ በኵራት ፡ ፈጽሞ ፡ ትቤዠዋለህ ፥ ያልነጻውንም ፡ እንስሳ ፡ በኵራት ፡ ትቤዠዋለህ ። ፲፮ ከአንድ ፡ ወር ፡ ጀምሮ ፡ የምትቤዠውን ፡ እንደ ፡ ግምትህ ፡ ትቤዠዋለህ ፤ ግምቱም ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ሰቅል ፡ ሚዛን ፡ አምስት ፡ ሰቅል ፡ ይሆናል ፤ እርሱም ፡ ሀያ ፡ አቦሊ ፡ ነው ። ፲፯ ነገር ፡ ግን ፡ የላም ፡ በኵራት ፡ ወይም ፡ የበግ ፡ በኵራት ፡ ወይም ፡ የፍየል ፡ በኵራት ፡ አትቤዠም ፤ የተቀደሱ ፡ ናቸው ፤ ደማቸውን ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ትረጨዋለህ ፥ ስባቸውንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ ለእሳት ፡ ቍርባን ፡ ታቃጥለዋለህ ። ፲፰ ሥጋቸውም ፡ ለአንተ ፡ ይሆናል ፤ እንደ ፡ መወዝወዝ ፡ ፍርምባ ፡ እንደ ፡ ቀኙም ፡ ወርች ፡ ለአንተ ፡ ይሆናል ። ፲፱ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከተቀደሰው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አንሥተው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያቀረቡትን ፡ ለአንተ ፡ ከአንተም ፡ ጋር ፡ ለወንዶችና ፡ ለሴቶች ፡ ልጆችህ ፡ ድርሻ ፡ እንዲሆን ፡ ለዘላለም ፡ ሰጥቼሃለሁ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለአንተ ፡ ከአንተም ፡ ጋር ፡ ለዘርህ ፡ የጨው ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ለዘላለም ፡ ነው ።

፳ እግዚአብሔርም ፡ አሮንን ፡ አለው ፡— በምድራቸው ፡ ርስት ፡ በመካከላቸውም ፡ ድርሻ ፡ አይሆንልህም ፤ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ድርሻህና ፡ ርስትህ ፡ እኔ ፡ ነኝ ። ፳፩ ለሌዊም ፡ ልጆች ፥ እነሆ ፥ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ አገልግሎት ፡ ስለሚያገለግሉ ፥ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ አሥራት ፡ ርስት ፡ አድርጌ ፡ ሰጥቼአለሁ ። ፳፪ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ኃጢአትን ፡ እንዳይሸከሙ ፡ እንዳይሞቱም ፥ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ አይቅረቡ ። ፳፫ ሌዋውያን ፡ ግን ፡ የመገናኛውን ፡ ድንኳን ፡ አገልግሎት ፡ ይሥሩ ፥ እነርሱም ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ይሸከማሉ ፤ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ ለዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ይሆናል ፤ በእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ርስት ፡ አይወርሱም ። ፳፬ ለእግዚአብሔር ፡ የማንሣት ፡ ቍርባን ፡ የሚያቀርቡትን ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ አሥራት ፡ ለሌዋውያን ፡ ርስት ፡ አድርጌ ፡ ሰጥቼአለሁ ፤ ስለዚህ ፡— በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ርስት ፡ አይወርሱም ፡ አልኋቸው ።

፳፭ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ፳፮ ለሌዋውያን ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ለእናንተ ፡ ርስት ፡ አድርጌ ፡ የሰጠኋችሁን ፡ አሥራት ፡ በተቀበላችሁ ፡ ጊዜ ፥ ለእግዚአብሔር ፡ ለማንሣት ፡

ቍርባን ፡ የአሥራት ፡ አሥራት ፡ ታቀርባላችሁ ።
፳፯ የማንሣት ፡ ቍርባናችሁም ፡ እንደ ፡ አውድማው ፡
እህልና ፡ እንደ ፡ ወይን ፡ መጭመቂያው ፡ ፍሬ ፡
፳፰ ይቈጠርላችኋል ። እንዲሁ ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡
ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከምትቀበሉት ፡ አሥራት ፡
ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የማንሣት ፡ ቍርባን ፡
ታቀርባላችሁ ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ የማንሣት ፡
፳፱ ቍርባን ፡ ለካህኑ ፡ ለአሮን ፡ ትሰጣላችሁ ። ከም
ትቀበሉት ፡ ስጦታ ፡ ሁሉ ፥ ከተመረጠው ፡ ከተ
ቀደሰውም ፡ ድርሻ ፡ ሁሉ ፥ የእግዚአብሔርን ፡
የማንሣት ፡ ቍርባን ፡ ሁሉ ፡ ታቀርባላችሁ ።
፴ ስለዚህ ፡ ትላቸዋለህ ፡— ከእርሱ ፡ የተመረጠ
ውን ፡ ባነሣችሁ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ አውድማው ፡ እህ
ልና ፡ እንደ ፡ ወይን ፡ መጭመቂያው ፡ ፍሬ ፡
፴፩ ለሌዋውያን ፡ ይቈጠራል ። እናንተም ፡ ቤተ ፡
ሰቦቻችሁም ፥ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡
የማገልገላችሁ ፡ ዋጋ ፡ ነውና ፡ በሁሉ ፡ ስፍራ ፡
፴፪ ትበሉታላችሁ ። የተመረጠውንም ፡ ከእርሱ ፡
ባነሣችሁ ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ኃጢአትን ፡ አት
ሸከሙም ፤ እንዳትሞቱም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
የቀደሱትን ፡ አታረክሱም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ እን
፪ ዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— እግዚአብሔር ፡
ያዘዘው ፡ የሕጉ ፡ ትእዛዝ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ መልክ
ሚቱን ፥ ነውርም ፡ የሌለባትን ፥ ቀንበርም ፡ ያል
ተጫነባትን ፡ ቀይ ፡ ጊደር ፡ ያመጡልህ ፡ ዘንድ ፡
፫ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ንገራቸው ። እርስዋንም ፡
ለካህኑ ፡ ለአልዓዛር ፡ ትሰጣላችሁ ፥ እርስዋንም ፡
ከሰፈር ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ይወስዳታል ፥ አንድ ፡
፬ ሰውም ፡ በፊቱ ፡ ያርዳታል ። ካህኑም ፡ አልዓ
ዛር ፡ ከደምዋ ፡ በጣቱ ፡ ይወስዳል ፥ ከደምዋም ፡
ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ፊት ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡
፭ ይረጫል ። ጊደሪቱም ፡ በፊቱ ፡ ትቃጠላለች ፤
ቁርበትዋም ፡ ሥጋዋም ፡ ደምዋም ፡ ፈርስዋም ፡
፮ ይቃጠላል ። ካህኑም ፡ የዝግባ ፡ እንጨት ፡ ሂሶ
ጵም ፡ ቀይ ፡ ግምጃም ፡ ወስዶ ፡ ጊደሪቱ ፡ በም
ትቃጠልበት ፡ እሳት ፡ መካከል ፡ ይጥለዋል ።
፯ ካህኑም ፡ ልብሱን ፡ ያጥባል ፥ ገላውንም ፡ በውኃ ፡
ይታጠባል ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሰፈሩ ፡
ይገባል ፤ ካህኑም ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ርኩስ ፡ ይሆ
፰ ናል ። ያቃጠላትም ፡ ሰው ፡ ልብሱን ፡ በውኃ ፡
ያጥባል ፥ ገላውንም ፡ በውኃ ፡ ይታጠባል ፥
፱ እስከ ፡ ማታም ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡ ይሆናል ። ንጹ
ሕም ፡ ሰው ፡ የጊደሪቱን ፡ አመድ ፡ ያከማቻል ፡
ከሰፈሩም ፡ ውጭ ፡ በንጹሕ ፡ ስፍራ ፡ ያኖረዋል ፤
ርኵሰትም ፡ ለሚያነጻ ፡ ውኃ ፡ ለእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ይጠበቃል ፤ ከኃጢአት ፡
፲ ለማንጻት ፡ የሚሆን ፡ ነው ። የጊደሪቱንም ፡
አመድ ፡ ያከማቸ ፡ ሰው ፡ ልብሱን ፡ ያጥባል ፡
እስከ ፡ ማታም ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡ ይሆናል ፤
ይህም ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በመካከላቸ
ውም ፡ ለሚኖር ፡ መጻተኛ ፡ ለዘላለም ፡ ሥር
ዓት ፡ ይሆናል ።

፲፩ የሞተውን ፡ ሰው ፡ በድን ፡ የሚነካ ፡ ሰባት ፡
፲፪ ቀን ፡ ርኩስ ፡ ይሆናል ፤ በዚህም ፡ ውኃ ፡ በሦ
ስተኛውና ፡ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ሁለመናውን ፡
ያጠራል ፥ ንጹሕም ፡ ይሆናል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በሦ
ስተኛውና ፡ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ሁለመናውን ፡
፲፫ ባያጠራ ፡ ንጹሕ ፡ አይሆንም ። የሞተውን ፡
ሰው ፡ በድን ፡ የነካ ፡ ሁለመናውን ፡ ባያጠራ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ማደሪያ ፡ ያረክሳል ፤ ያ ፡
ሰው ፡ ከእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ተለይቶ ፡ ይጠፋል ፤
በእርሱም ፡ ላይ ፡ የሚያነጻ ፡ ውኃ ፡ አልተረጨ
ምና ፡ ርኩስ ፡ ይሆናል ፤ ርኵሰቱ ፡ ገና ፡ በእ
ርሱ ፡ ላይ ፡ ነው ።

፲፬ ሰው ፡ በድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ቢሞት ፡ ሕጉ ፡
ይህ ፡ ነው ፤ ወደ ፡ ድንኳኑ ፡ የሚገባ ፡ ሁሉ ፡
በድንኳኑም ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ ሰባት ፡
፲፭ ቀን ፡ ርኩስ ፡ ይሆናል ። መክደኛው ፡ ያልታ
ሰረ ፡ የተከፈተ ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡ ነው ።
፲፮ በሜዳም ፡ በሰይፍ ፡ የተገደለውን ፡ ወይም ፡
የሞተውን ፡ በድን ፡ ወይም ፡ የሰውን ፡ አጥንት ፡
ወይም ፡ መቃብር ፡ የሚነካ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ርኩስ ፡
፲፯ ይሆናል ። ከኃጢአት ፡ ለማንጻት ፡ እንድትሆን ፡
ከተቃጠለችው ፡ ጊደር ፡ አመድ ፡ ለርኩሱ ፡ ይወ
ስዱለታል ፥ በዕቃውም ፡ ውስጥ ፡ የምንጭ ፡
፲፰ ውኃ ፡ ይቀላቀልበታል ። ንጹሕም ፡ ሰው ፡
ሂሶጱን ፡ ወስዶ ፡ በውኃው ፡ ውስጥ ፡ ያጠልቀ
ዋል ፤ በድንኳኑም ፥ በዕቃውም ፡ ሁሉ ፥ በዚ
ያም ፡ ባሉ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፥ አጥንቱንም ፡ ወይም ፡
የተገደለውን ፡ ወይም ፡ የሞተውን ፡ ወይም ፡
፲፱ መቃብሩን ፡ በነካው ፡ ላይ ፡ ይረጨዋል ፤ ንጹ
ሑም ፡ በሦስተኛውና ፡ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ በር
ኩሱ ፡ ላይ ፡ ይረጨዋል ፤ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡
ያጠራዋል ፤ እርሱም ፡ ልብሱን ፡ ያጥባል ፥ ገላ
ውንም ፡ በውኃ ፡ ይታጠባል ፥ በማታም ፡ ጊዜ ፡
ንጹሕ ፡ ይሆናል ።

፳ ሰውም ፡ ርኩስ ፡ ቢሆን ፡ ሁለመናውንም ፡ ባያ
ጠራ ፥ ያ ፡ ሰው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መቅደስ ፡
አርክሶአልና ፡ ከጉባኤው ፡ መካከል ፡ ተለይቶ ፡
ይጠፋል ፤ በሚያነጻ ፡ ውኃ ፡ አልተረጨም ፤
፳፩ ርኩስ ፡ ነው ። ይህም ፡ የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡
ይሆንላችኋል ፤ የሚያነጻውን ፡ ውኃ ፡ የሚ
ረጭ ፡ ሰው ፡ ልብሱን ፡ ያጥባል ፤ የሚያነጻው
ንም ፡ ውኃ ፡ የሚነካ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡
፳፪ ርኩስ ፡ ይሆናል ። ርኩሱም ፡ የሚነካው ፡ ነገር ፡
ሁሉ ፡ ርኩስ ፡ ይሆናል ፤ የሚነካውም ፡ ሰው ፡
እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ ርኩስ ፡ ይሆናል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ በመ
ጀመሪያው ፡ ወር ፡ ወደ ፡ ጺን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
መጡ ፤ ሕዝቡም ፡ በቃዴስ ፡ ተቀመጡ ፤ ማር
ያምም ፡ በዚያ ፡ ሞተች ፥ በዚያም ፡ ተቀበረች ።
፪ ለማኅበሩም ፡ ውኃ ፡ አልነበረም ፤ በሙሴና ፡
፫ በአሮንም ፡ ላይ ፡ ተሰበሰቡ ። ሕዝቡም ፡ ሙሴን ፡

ተጣሉት ፥ እንዲህም ፡ ብለው ፡ ተናገሩት ፡— ወንድሞቻችን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በሞቱ ፡ ፬፤ ጊዜ ፡ እኛም ፡ ምነው ፡ በሞትን ፡ ኖሮ ! እኛ ፡ ከብቶቻችንም ፡ በዚያ ፡ እንሞት ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ጉባኤ ፡ ወደዚህ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ፭፤ ለምን ፡ አመጣችሁ ? ወደዚህ ፡ ክፉ ፡ ስፍራ ፡ ታመጡን ፡ ዘንድ ፡ ከግብፅ ፡ ለምን ፡ አወጣችሁን ? ዘርና ፡ በለስ ፡ ወይንም ፡ ሮማንም ፡ የሌለበት ፡ ስፍራ ፡ ነው ፤ የሚጠጣም ፡ ውኃ ፡ የለበትም ። ፮፤ ሙሴና ፡ አሮንም ፡ ከጉባኤው ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ሄደው ፡ በግምባራቸው ፡ ወደቁ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ፯፤ ክብር ፡ ተገለጠላቸው ። እግዚአብሔርም ፡ ፰፤ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— በትርህን ፡ ውሰድ ፤ አንተና ፡ ወንድምህ ፡ አሮን ፡ ማኅበሩን ፡ ሰብስቡ ፥ ድንጋዩም ፡ ውኃን ፡ እንዲሰጥ ፡ እነርሱ ፡ ሲያዩ ፡ ተናገሩት ፤ ከድንጋዩም ፡ ውኃ ፡ ታወጣላቸዋለህ ፤ እንዲሁም ፡ ማኅበሩን ፡ ከብቶቻቸውንም ፡ ታጠጣላቸዋለህ ። ፱፤ ሙሴም ፡ እንደ ፡ ታዘዘ ፡ በትሩን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ወሰደ ።

፲፤ ሙሴና ፡ አሮንም ፡ ጉባኤውን ፡ በድንጋዩ ፡ ፊት ፡ ሰብስበው ፡— እናንተ ፡ ዓመፀኞች ፥ እንግዲህ ፡ ስሙ ፤ በውኑ ፡ ከዚህ ፡ ድንጋይ ፡ ውኃን ፡ ፲፩፤ እናወጣላችኋለን? አላቸው ። ሙሴም ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡ ድንጋዩን ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ በበትሩ ፡ መታው ፤ ብዙም ፡ ውኃ ፡ ወጣ ፥ ማኅበሩም ፡ ፲፪፤ ከብቶቻቸውም ፡ ጠጡ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡— በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ትቀድሱኝ ፡ ዘንድ ፡ በእኔ ፡ አላመናችሁምና ፡ ስለዚህ ፡ ወደ ፡ ሰጠኋቸው ፡ ምድር ፡ ይህን ፡ ፲፫፤ ጉባኤ ፡ ይዛችሁ ፡ አትገቡም ፡ አላቸው ። የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ጠብ ፡ ያደረጉበት ፥ እርሱም ፡ ቅዱስ ፡ መሆኑን ፡ የገለጠበት ፡ ይህ ፡ የመሪባ ፡ ውኃ ፡ ነው ።

፲፬፤ ሙሴም ፡ ከቃዴስ ፡ ወደ ፡ ኤዶምያስ ፡ ንጉሥ ፡ መልእክተኞችን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ላከ ፡— ወንድምህ ፡ እስራኤል ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ያገኘን ፲፭፤ ን ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ታውቃለህ ፤ አባቶቻችን ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ወረዱ ፥ በግብፅም ፡ እጅግ ፡ ዘመን ፡ ተቀመጥን ፡ ግብፃውያንም ፡ እኛ ፲፮፤ ንና ፡ አባቶቻችንን ፡ በደሉ ፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በጮኽን ፡ ጊዜ ፡ ድምፃችንን ፡ ሰማ ፥ መልአኩንም ፡ ሰድዶ ፡ ከግብፅ ፡ አወጣን ፤ እነሆም ፥ በምድርህ ፡ ዳርቻ ፡ ባለችው ፡ ከተማ ፡ ፲፯፤ በቃዴስ ፡ ተቀምጠናል ። እባክህ ፥ በምድርህ ፡ ላይ ፡ እንለፍ ፤ ወደ ፡ እርሻም ፡ ወደ ፡ ወይንም ፡ አንገባም ፥ ከጕድጓዶችም ፡ ውኃን ፡ አንጠጣም ፤ በንጉሡ ፡ ጐዳና ፡ እንሄዳለን ፥ ዳርቻህንም ፡ እስክናልፍ ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ ፲፰፤ አንልም ። ኤዶምያስም ፡— በሰይፍ ፡ እንዳልገጥምህ ፡ በምድሬ ፡ ላይ ፡ አታልፍም ፡ አለው ። ፲፱፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡— በጐዳናው ፡ እንሄዳለን ፥ እኔም ፡ ከብቶቼም ፡ ከውኃህ ፡ ብንጠጣ ፡ ዋጋውን ፡ እንከፍላለን ፥ ሌላም ፡ ምንም ፡ አናደርግም ፤ ብቻ ፡ በእግራችን ፡ እንለፍ ፡ አሉት ። ፳፤ እርሱም ፡— አታልፍም ፡ አለ ። ኤዶምያስም ፡ በብዙ ፡ ሕዝብና ፡ በጽኑ ፡ እጅ ፡ ሊገጥመው ፡ ፳፩፤ ወጣ ። ኤዶምያስም ፡ እስራኤል ፡ በዳርቻው ፡ እንዳያልፍ ፡ ከለከለ ፤ ስለዚህ ፡ እስራኤል ፡ ከእርሱ ፡ ተመለሰ ።

፳፪፤ ከቃዴስም ፡ ተጓዙ ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ሖር ፡ ተራራ ፡ መጡ ። ፳፫፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ በኤዶምያስ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ባለው ፡ በሖር ፡ ተራራ ፡ ፳፬፤ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— አሮን ፡ ወደ ፡ ወገኑ ፡ ይከማች ፤ በመሪባ ፡ ውኃ ፡ ዘንድ ፡ በቃሌ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ዐመፃችሁ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ሰጠኋት ፡ ምድር ፡ አይገባም ። ፳፭፤ አሮንንና ፡ ልጁን ፡ አልዓዛርን ፡ ይዘህ ፡ ወደ ፡ ሖር ፡ ፳፮፤ ተራራ ፡ ላይ ፡ አምጣቸው ፤ ከአሮንም ፡ ልብሱን ፡ አውጣ ፥ ልጁንም ፡ አልዓዛርን ፡ አልብሰው ፤ አሮንም ፡ ወደ ፡ ወገኑ ፡ ይከማች ፥ በዚያም ፡ ፳፯፤ ይሙት ። ሙሴም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘ ፡ አደረገ ፤ ማኅበሩም ፡ ሁሉ ፡ እያዩ ፡ ወደ ፡ ሖር ፡ ፳፰፤ ተራራ ፡ ወጡ ። ሙሴም ፡ የአሮንን ፡ ልብስ ፡ አወጣ ፥ ልጁንም ፡ አልዓዛርን ፡ አለበሰው ፤ አሮንም ፡ በዚያ ፡ በተራራው ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ሞተ ፤ ሙሴና ፡ አልዓዛርም ፡ ከተራራው ፡ ወረዱ ። ፳፱፤ ማኅበሩም ፡ ሁሉ ፡ አሮን ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፥ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ለአሮን ፡ ሠላሳ ፡ ቀን ፡ አለቀሱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩፤ በደቡብም ፡ በኩል ፡ ተቀምጦ ፡ የነበረው ፡ ከነዓናዊው ፡ የዓራድ ፡ ንጉሥ ፡ በአታሪም ፡ መንገድ ፡ እስራኤል ፡ እንደ ፡ መጡ ፡ ሰማ ፤ ከእስራኤልም ፡ ጋር ፡ ሰልፍ ፡ አደረገ ፡ ከእነርሱም ፡ ፪፤ ምርኮ ፡ ማረከ ። እስራኤልም ፡ ለእግዚአብሔር ፡— እነዚህን ፡ አሳልፈህ ፡ በእጄ ፡ ብትሰጣቸው ፡ ከተሞቻቸውን ፡ እርም ፡ ብዬ ፡ አጠፋለሁ ፡ ብሎ ፡ ስእለት ፡ ተሳለ ። ፫፤ እግዚአብሔርም ፡ የእስራኤልን ፡ ድምፅ ፡ ሰማ ፥ ከነዓናውያንንም ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፤ እነርሱንም ፡ ከተሞቻቸውንም ፡ እርም ፡ ብለው ፡ አጠፉ ፤ የዚያንም ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ ሔርማ ፡ ብለው ፡ ጠሩት ።

፬፤ ከሖርም ፡ ተራራ ፡ ከኤዶምያስ ፡ ምድር ፡ ርቀው ፡ ሊዞሩ ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ መንገድ ፡ ተጓዙ ፤ የሕዝቡም ፡ ሰውነት ፡ ከመንገዱ ፡ የተ ፭፤ ነሣ ፡ ደከመ ። ሕዝቡም ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በሙሴ ፡ ላይ ፡— በምድረ ፡ በዳ ፡ እንሞት ፡ ዘንድ ፡ ከግብፅ ፡ ለምን ፡ አወጣችሁን ? እንጀራ ፡ የለም ፥ ውኃ ፡ የለም ! ሰውነታችንም ፡ ይህን ፡ ቀላል ፡ ፮፤ እንጀራ ፡ ተጸየፈ ፡ ብለው ፡ ተናገሩ ። እግዚአብሔርም ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ እባቦችን ፡ ሰደደ ፥ ሕዝቡንም ፡ ነደፉ ፤ ከእስራኤልም ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ፯፤ ሞቱ ። ሕዝቡም ፡ ወደ ፡ ሙሴ ፡ መጥተው ፡— በእግዚአብሔርና ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ተናገ

ርን ፡ በድለናል ፤ እባቦችን ፡ ከእኛ ፡ ያርቅልን ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸልይልን ፡ አሉት ። ሙሴም ፡ ስለ ፡ ሕዝቡ ፡ ጸለየ ። ፰ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፦ እባብን ፡ ሥርተህ ፡ በዓላማ ፡ ላይ ፡ ሰቅል ፤ የተነደፈውም ፡ ሁሉ ፡ ሲያየው ፡ በሕይ ፱ ወት ፡ ይኖራል ፡ አለው ። ሙሴም ፡ የናሱን ፡ እባብ ፡ ሠርቶ ፡ በዓላማ ፡ ላይ ፡ ሰቀለ ፤ እባብም ፡ የነደፈችው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የናሱን ፡ እባብ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ዳነ ።

፲ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ተጓዙ ፥ በኦቦትም ፡ ፲፩ ሰፈሩ ። ከኦቦትም ፡ ተጕዘው ፡ በሞዓብ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ባለችው ፡ ምድረ ፡ በዳ ፥ በፀሐይ ፡ ፲፪ መውጫ ፡ በኢዬዓባሪም ፡ ሰፈሩ ። ፲፫ ከዚያም ፡ ተጕዘው ፡ በዘሬድ ፡ ሸለቆ ፡ ሰፈሩ ። ከዚያም ፡ ተጕዘው ፡ ከአሞራውያን ፡ ዳርቻ ፡ በሚወጣው ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ውስጥ ፡ በአርኖን ፡ ማዶ ፡ ሰፈሩ ፤ አርኖን ፡ በሞዓብና ፡ በአሞራውያን ፡ ፲፬ መካከል ፡ ያለ ፡ የሞዓብ ፡ ዳርቻ ፡ ነውና ። ስለ ዚህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ የጦርነት ፡ መጽሐፍ ፡ እንዲህ ፡ ተብሎ ፦

ዋሄብ ፡ በሱፋ ፥
የአርኖንም ፡ ሸለቆች ፥
፲፭ ወደ ፡ ዔር ፡ ማደሪያ ፡ የሚወርድ ፡
በሞዓብም ፡ ዳርቻ ፡ የሚጠጋ ፡
የሸለቆች ፡ ፈሳሽ ።

፲፮ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ብኤር ፡ ተጓዙ ፤ ይኸውም ፡ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፦ ሕዝቡን ፡ ሰብስብ ፡ ውኃንም ፡ እሰጣቸዋለሁ ፡ ብሎ ፡ የተናገረለት ፡ ጕድጓድ ፡ ነው ።

፲፯ በዚያም ፡ ጊዜ ፡ እስራኤል ፡ ይህን ፡ መዝሙር ፡ ዘመረ ፦

አንተ ፡ ምንጭ ፡ ሆይ ፥ ፍለቅ ፤ እናንተ ፡
ዘምሩለት ፤
፲፰ በበትረ ፡ መንግሥት ፡ በበትራቸውም ፡
የሕዝብ ፡ አዛውንቶች ፡ ያጐደጐዱት ፥
አለቆችም ፡ የቈፈሩት ፡ ጕድጓድ ።

፲፱ ከምድረ ፡ በዳም ፡ ወደ ፡ መቴና ፡ ተጓዙ ፤ ከመቴናም ፡ ወደ ፡ ነሃሊኤል ፥ ከነሃሊኤልም ፡ ወደ ፡ ፳ በሞት ፥ ከባሞትም ፡ ምድረ ፡ በዳውን ፡ ከላይ ፡ ወደሚመለከተው ፡ ወደ ፡ ፈስጋ ፡ ተራራ ፡ ራስ ፡ በሞዓብ ፡ በረሀ ፡ ወዳለው ፡ ሸለቆ ፡ ተጓዙ ።

፳፩ ፳፪ እስራኤልም ፦ በምድርህ ፡ ላይ ፡ እንለፍ ፤ ወደ ፡ እርሻና ፡ ወደ ፡ ወይን ፡ ቦታ ፡ አንገባም ፤ ከጕድጓድም ፡ ውኃን ፡ አንጠጣም ፤ ከምድርህ ፡ ዳርቻ ፡ እስክንወጣ ፡ ድረስ ፡ በንጉሥ ፡ ጐዳና ፡ እንሄዳለን ፡ ብለው ፡ ወደ ፡ አሞራውያን ፡ ንጉሥ ፡ ፳፫ ወደ ፡ ሴዎን ፡ መልእክተኞችን ፡ ላኩ ። ሴዎንም ፡ እስራኤል ፡ በምድሩ ፡ ላይ ፡ ያልፍ ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ አለ ፤ ሴዎንም ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰበ ፥ እስራኤልንም ፡ ለመውጋት ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወጣ ፥ ወደ ፡ ያሀጽም ፡ መጣ ፥ ከእስራኤ ፳፬ ልም ፡ ጋር ፡ ተዋጋ ። እስራኤልም ፡ በሰይፍ ፡ መታው ፥ ምድሩንም ፡ ከአርኖን ፡ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አሞን ፡ ልጆች ፡ እስከ ፡ ያቦቅ ፡ ድረስ ፡ ወረሰ ፤ የአሞንም ፡ ልጆች ፡ ዳርቻ ፡ የጸና ፡ ነበረ ። ፳፭ እስራኤልም ፡ እነዚህን ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ወሰደ ፤ እስራኤልም ፡ በአሞራውያን ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ በሐሴቦንና ፡ በመንደሮቹ ፡ ሁሉ ፡ ተቀመጠ ። ፳፮ ሐሴቦንም ፡ የአሞራውያን ፡ ንጉሥ ፡ የሴዎን ፡ ከተማ ፡ ነበረ ፤ እርሱም ፡ የፊተኛውን ፡ የሞዓብን ፡ ንጉሥ ፡ ወግቶ ፡ እስከ ፡ አርኖን ፡ ድረስ ፡ ፳፯ ምድሩን ፡ ሁሉ ፡ ከእጁ ፡ ወስዶ ፡ ነበር ። ስለ ዚህ ፡ በምሳሌ ፡ እንዲህ ፡ ተብሎ ፡ ተነገረ ፦

ወደ ፡ ሐሴቦን ፡ ኑ ፤
የሴዎን ፡ ከተማ ፡ ይሠራ ፥ ይመሥረት ፤
፳፰ እሳት ፡ ከሐሴቦን ፥ ነበልባልም ፡ ከሴዎን ፡
ከተማ ፡ ወጣ ፤
የሞዓብን ፡ ዔር ፥ የአርኖንን ፡ ተራራ ፡ አለ
ቆች ፡ በላ ፤
፳፱ ሞዓብ ፡ ሆይ ፥ ወዮልህ !
የካሞስ ፡ ሕዝብ ፡ ሆይ ፥ ጠፋህ ፤
ወንዶች ፡ ልጆቹን ፡ ለሽሽት ፥ ሴቶች ፡
ልጆቹንም ፡ ለምርኮ ፥
ለአሞራውያን ፡ ንጉሥ ፡ ለሴዎን ፡ ሰጠ ።
፴ ገተርናቸው ፤ ከሐሴቦን ፡ እስከ ፡ ዲቦን ፡
ድረስ ፡ ጠፋ ፤
ኖፋም ፡ እስኪደርሱ ፡ እስከ ፡ ሜድባ ፡ አፈ
ረስናቸው ።

፴፩ እስራኤልም ፡ እንደዚህ ፡ በአሞራውያን ፡ ምድር ፡ ፴፪ ተቀመጡ ። ሙሴም ፡ ሰላዮችን ፡ ወደ ፡ ኢያዜር ፡ ሰደደ ፤ መንደሮችዋንም ፡ ወሰዱ ፥ በዚያም ፡ የነበሩትን ፡ አሞራውያን ፡ አባረሩ ።

፴፫ ተመልሰውም ፡ በባሳን ፡ መንገድ ፡ ወጡ ፤ የባሳንም ፡ ንጉሥ ፡ ዐግ ፡ ከሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ፴፬ በኤድራይ ፡ ይወጋቸው ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፦ እርሱንና ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ምድሩንም ፡ አሳልፌ ፡ በእጅህ ፡ ሰጥቼ አለሁና ፡ አትፍራው ፤ በሐሴቦንም ፡ በተቀመጠው ፡ በአሞራውያን ፡ ንጉሥ ፡ በሴዎን ፡ እን ዳደረግህ ፡ እንዲሁ ፡ ታደርግበታለህ ፡ አለው ። ፴፭ እርሱንና ፡ ልጆቹን ፡ ሕዝቡንም ፡ ሁሉ ፡ መቱ ፡ ሰውም ፡ አልቀረለትም ፤ ምድሩንም ፡ ወረሱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ተጓዙ ፥ በኢያሪኮ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ባለው ፡ በሞዓብ ፡ ሜዳ ፡ ሰፈሩ ።

፪ የሴፎር ፡ ልጅ ፡ ባላቅ ፡ እስራኤል ፡ በአሞራ ፫ ውያን ፡ ላይ ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፡ አየ ። ብዙም ፡ ነበረና ፡ ሞዓብ ፡ ከሕዝቡ ፡ እጅግ ፡ ፈራ ፤ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ የተነሣ ፡ ሞዓብ ፡ ደነገጠ ። ፬ ሞዓብም ፡ የምድያምን ፡ ሽማግሌዎች ፦ በሬ ፡ የለመለመውን ፡ ሣር ፡ እንደሚጨርስ ፡ ይህ ፡ ጭፍራ ፡ በዙሪያችን ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ይጨርሳል ፡ አላቸው ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ የሴፎር ፡ ልጅ ፡ ባላቅ ፡ የሞዓብ ፡ ንጉሥ ፡ ነበረ ። ፭ በወንዙ ፡ አጠገብ ፡ ባለችው ፡ በሕዝቡ ፡ ልጆች ፡ ምድር ፡ በፋቱራ ፡ ወደ ፡ ተቀመጠው ፡ ወደ ፡

ቢያር ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ በለዓም ፡— እነሆ ÷ ከግብፅ ፡ የወጣ ፡ ሕዝብ ፡ አለ ፤ እነሆም ÷ የምድሩን ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ሸፈኑ ÷ በአቅራቢያችንም ፡ ተቀ ምጦአል ፤ አሁንም ፡ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ከእኔ ፡ ይበ ልጣልና ፡ ልወጋቸውና ፡ ከምድሪቱ ፡ ላሳድዳ ቸው ፡ እችል ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ እባክህ ÷ ና ፡ ርገም ልኝ ፤ አንተ ፡ የመረቅኸው ፡ ምሩቅ ፡ የረገም ኸውም ፡ ርጉም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አውቃለሁና ፡ ብሎ ፡ ይጠሩት ፡ ዘንድ ፡ መልእክተኞቹን ፡ ላከ ።

፯ የሞዓብ ፡ ሽማግሌዎችና ፡ የምድያም ፡ ሽማ ግሌዎችም ፡ የምዋርቱን ፡ ዋጋ ፡ በእጃቸው ፡ ይዘው ፡ ሄዱ ፤ ወደ ፡ በለዓምም ፡ መጡ ÷ የበ ላቅንም ፡ ቃል ፡ ነገሩት ። ፰ እርሱም ፡— ዛሬ ፡ ሌሊት ፡ በዚህ ፡ እደሩ ÷ እግዚአብሔርም ፡ እን ደሚነግረኝ ፡ እመልስላችኋለሁ ፡ አላቸው ፤ የሞ ዓብም ፡ አለቆች ፡ በበለዓም ፡ ዘንድ ፡ ተቀመጡ ። ፱ እግዚአብሔርም ፡ ወደ ፡ በለዓም ፡ መጥቶ ፡— እነዚህ ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ እነማን ፡ ናቸው ? አለው ። ፲፣፲፩ በለዓምም ፡ እግዚአብሔ ርን ፡— የሞዓብ ፡ ንጉሥ ፡ የሴፎር ፡ ልጅ ፡ በላቅ ፡— እነሆ ÷ ከግብፅ ፡ የወጣ ፡ ሕዝብ ፡ የምድርን ፡ ፊት ፡ ሸፈኑ ÷ አሁንም ፡ ና ፡ እርሱንም ፡ ርገም ልኝ ፤ ምናልባት ፡ እወጋው ፡ አሳድደውም ፡ ዘንድ ፡ እችል ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ልኮአል ፡ አለው ። ፲፪ እግዚአብሔርም ፡ በለዓ ምን ፡— ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ አትሂድ ፤ የተባረከ ፡ ነውና ፡ ሕዝቡን ፡ አትረግምም ፡ አለው ። ፲፫ በለ ዓምም ፡ ሲነጋ ፡ ተነሥቶ ፡ የበላቅን ፡ አለቆች ፡— ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እሄድ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ አልፈቀደምና ፡ ወደ ፡ ምድራችሁ ፡ ሂዱ ፡ አላ ቸው ። ፲፬ የሞዓብ ፡ አለቆች ፡ ተነሡ ÷ ወደ ፡ በላ ቅም ፡ መጥተው ፡— በለዓም ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ አልፈቀደም ፡ አሉት ።

፲፭ በላቅም ፡ ደግሞ ፡ ከፊተኞች ፡ የበዙና ፡ የከ በሩ ፡ ሌሎችን ፡ አለቆች ፡ ሰደደ ። ፲፮፣፲፯ ወደ ፡ በለዓ ምም ፡ መጥተው ፡— የሴፎር ፡ ልጅ ፡ በላቅ ፡— ክብርህን ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ አደርገዋለሁና ÷ የተ ናገርኸውንም ፡ ሁሉ ፡ አደርግልሃለሁና ፡ እባ ክህ ÷ ወደ ፡ እኔ ፡ ትመጣ ፡ ዘንድ ፡ ምንም ፡ አይ ከልከልህ ፤ እባክህ ÷ ና ÷ ይህን ፡ ሕዝብ ፡ ርገ ምልኝ ፡ አለ ፡ ብለው ፡ ነገሩት ። ፲፰ በለዓምም ፡ መልሶ ፡ የበላቅን ፡ ባሪያዎች ፡— በላቅ ፡ በቤቱ ፡ የሞላውን ፡ ወርቅና ፡ ብር ፡ ቢሰጠኝ ÷ በትንሹ ፡ ወይም ፡ በትልቁ ፡ ቢሆን ፡ የአምላኬን ፡ የእግ ዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ እተላለፍ ፡ ዘንድ ፡ አይቻ ለኝም ፤ ፲፱ አሁንም ፡ እግዚአብሔር ፡ ደግሞ ፡ የሚ ነግረኝን ፡ አውቅ ፡ ዘንድ ÷ እባካችሁ ÷ ዛሬ ፡ ሌሊት ፡ ደግሞ ፡ በዚህ ፡ እደሩ ፡ አላቸው ። ፳ እግዚአብሔርም ፡ ወደ ፡ በለዓም ፡ በሌሊት ፡ መጥቶ ፡— ሰዎቹ ፡ ይጠሩህ ፡ ዘንድ ፡ መጥተው ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ ተነሣ ፡ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ሂድ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የምነግርህን ፡ ቃል ፡ ብቻ ፡ ታደር ጋለህ ፡ አለው ።

፳፩ በለዓምም ፡ ሲነጋ ፡ ተነሣ ÷ አህያይቱንም ፡ ጭኖ ፡ ከሞዓብ ፡ አለቆች ፡ ጋር ፡ ሄደ ። ፳፪ እር ሱም ፡ ስለ ፡ ሄደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተቈጣ ፤ የእ ግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ሊቋቋመው ፡ በመ ንገድ ፡ ላይ ፡ ቆመ ። እርሱም ፡ በአህያይቱ ፡ ላይ ÷ ሁለቱም ፡ ሎሌዎቹ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበሩ ። ፳፫ አህያይቱም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መልአክ ፡ በመ ንገድ ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡ የተመዘዘም ፡ ሰይፍ ፡ በእጁ ፡ ይዞ ፡ አየች ፤ ከመንገዱም ፡ ፈቀቅ ፡ ብላ ፡ ወደ ፡ እርሻው ፡ ውስጥ ፡ ገባች ፤ በለዓምም ፡ ወደ ፡ መንገድ ፡ ይመልሳት ፡ ዘንድ ፡ አህያይቱን ፡ መታት ። ፳፬ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ከወ ይኑ ፡ በታዎች ፡ መካከል ፡ በወዲያና ፡ በወዲህ ፡ ወገን ፡ ግንብ ፡ በነበረበት ፡ በጠባብ ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ ቆመ ። ፳፭ አህያይቱም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መልአክ ፡ አይታ ፡ ወደ ፡ ቅጥሩ ፡ ተጠጋች ÷ የበ ለዓምንም ፡ እግር ፡ ከቅጥሩ ፡ ጋር ፡ አጣበቀች ፤ እርሱም ፡ ደግሞ ፡ መታት ። ፳፮ የእግዚአብሔ ርም ፡ መልአክ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ሄደ ÷ በቀኝና ፡ በግራ ፡ መተላለፊያ ፡ በሌለበት ፡ በጠባብ ፡ ስፍራ ፡ ቆመ ። ፳፯ አህያይቱም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መል አክ ፡ አየች ÷ ከበለዓምም ፡ በታች ፡ ተኛች ፤ በለዓምም ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ÷ አህያይቱንም ፡ በበትሩ ፡ ደበደባት ። ፳፰ እግዚአብሔርም ፡ የአህ ያይቱን ፡ አፍ ፡ ከፈተ ÷ በለዓምንም ፡— ሦስት ፡ ጊዜ ፡ የመታኸኝ ፡ ምን ፡ አድርጌብህ ፡ ነው ? አለችው ። ፳፱ በለዓምም ፡ አህያይቱን ፡— ስላላገ ጥሽብኝ ፡ ነው ፤ በእጄስ ፡ ሰይፍ ፡ ቢኖር ፡ አሁን ፡ በገደልሁሽ ፡ ነበር ፡ አላት ። ፴ አህያይቱም ፡ በለ ዓምን ፡— ከብዙ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ የምትቀመጥብኝ ፡ አህያህ ፡ አይደለሁ ምን ? በውኑ ፡ እንዲህ ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ ልማዴ ፡ ነበረን ? አለችው ። እርሱም ፡— እን ዲህ ፡ አላደረግሽብኝም ፡ አላት ።

፴፩ እግዚአብሔርም ፡ የበለዓምን ፡ ዓይኖች ፡ ከፈተ ፤ የእግዚአብሔርን ፡ መልአክ ፡ በመን ገድ ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡ የተመዘዘም ፡ ሰይፍ ፡ በእጁ ፡ ይዞ ፡ አየ ፤ ሰገደም ÷ በግምባሩም ፡ ወደቀ ። ፴፪ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡— አህያህን ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ለምን ፡ መታህ ? እነሆ ÷ መንገ ድህ ፡ በፊቴ ፡ ጠማማ ፡ ነውና ፡ እቋቋምህ ፡ ዘንድ ፡ ወጥቼአለሁ ፤ ፴፫ አህያይቱም ፡ አይታኝ ፡ ከፊቴ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ፈቀቅ ፡ አለች ፤ ከፊቴስ ፡ ፈቀቅ ፡ ባላለች ፡ በእውነት ፡ አሁን ፡ አንተን ፡ በገደል ሁህ ÷ እርስዋንም ፡ ባዳንኋት ፡ ነበር ፡ አለው ። ፴፬ በለዓምም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መልአክ ፡— በድ ያለሁ ፤ አንተ ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ በፊቴ ፡ እንደ ፡ ቆምህብኝ ፡ አላወቅሁም ፤ እንግዲህም ፡ አሁን ፡ አትወድድ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እመለሳለሁ ፡ አለው ። ፴፭ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ በለዓምን ፡— ከሰዎቹ ፡ ጋር ፡ ሂድ ÷ ነገር ፡ ግን ፡ የምናገርህን ፡ ቃል ፡ ብቻ ፡ ትናገራለህ ፡ አለው ። በለዓምም ፡ ከባላቅ ፡ አለቆች ፡ ጋር ፡ ሄደ ።

፴፮ በላቅም ፡ በለዓም ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ በአርኖን ፡ ዳር ፡ ዳርቻ ፡ በመጨረሻ ፡ ወዳ

ለችው ፡ ወደ ፡ ሞዓብ ፡ ከተማ ፡ ሊገናኘው ፡
፴፯ ወጣ ። ባላቅም ፡ በለዓምን ፡— በውኑ ፡ አንተን ፡
ለመጥራት ፡ አልላክሁብህምን ? ለምንስ ፡ ወደ ፡
እኔ ፡ አልመጣህም ? በውኑ ፡ አንተን ፡ ለማክ
፴፰ በር ፡ እኔ ፡ አልችልምን ? አለው ። በለዓምም ፡
ባላቅን ፡— እነሆ ፥ ወደ ፡ አንተ ፡ መጥቼአለሁ ፤
በውኑ ፡ አሁን ፡ አንዳችን ፡ ነገር ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡
እችላለሁን ? እግዚአብሔር ፡ በአፌ ፡ የሚያደ
ርገውን ፡ ቃል ፡ እርሱን ፡ እናገራለሁ ፡ አለው ።
፴፱ በለዓምም ፡ ከባላቅ ፡ ጋር ፡ ሄደ ፥ ወደ ፡ ቂርያት
፵ ሐጸትም ፡ መጡ ። ባላቅም ፡ በሬዎችንና ፡ በጎ
ችን ፡ አርዶ ፡ ወደ ፡ በለዓም ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡
፵፩ ወዳሉት ፡ አለቆች ፡ ላከ ። በነጋውም ፡ ባላቅ ፡
በለዓምን ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ በኣል ፡ ኮረብታ ፡ መስ
ገጃ ፡ አወጣው ፤ በዚያም ፡ ሆኖ ፡ የሕዝቡን ፡
ዳርቻ ፡ አየ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ በለዓምም ፡ ባላቅን ፡— ሰባት ፡ መሠዊያ ፡
በዚህ ፡ ሥራልኝ ፥ ሰባትም ፡ ወይፈን ፡ ሰባትም ፡
አውራ ፡ በግ ፡ በዚህ ፡ አዘጋጅልኝ ፡ አለው ።
፪ ባላቅም ፡ በለዓም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ አደረገ ፤
ባላቅና ፡ በለዓምም ፡ በየመሠዊያው ፡ ላይ ፡
አንድ ፡ ወይፈንና ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፡ አሳ
፫ ረጉ ። በለዓምም ፡ ባላቅን ፡— በመሥዋዕትህ ፡
ዘንድ ፡ ቆይ ፥ እኔም ፡ እሄዳለሁ ፤ ምናልባት ፡
እግዚአብሔር ፡ ሊገናኘኝ ፡ ይመጣል ፤ እርሱም ፡
የሚገልጥልኝን ፡ እነግርሃለሁ ፡ አለው ። ወደ ፡
፬ ጉብታም ፡ ሄደ ። እግዚአብሔርም ፡ ከበለዓም ፡
ጋር ፡ ተገናኘ ፤ እርሱም ፡— ሰባት ፡ መሠዊያ
ዎች ፡ አዘጋጀሁ ፥ በየመሠዊያውም ፡ ላይ ፡
አንድ ፡ ወይፈንና ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፡ አሳ
፭ ረግሁ ፡ አለው ። እግዚአብሔርም ፡ ቃልን ፡ በበ
ለዓም ፡ አፍ ፡ አድርጎ ፡— ወደ ፡ ባላቅ ፡ ተመ
፮ ለስ ፥ እንዲህም ፡ በል ፡ አለው ። ወደ ፡ እርሱም ፡
ተመለሰ ፥ እነሆም ፥ እርሱና ፡ የሞዓብ ፡ አለቆች ፡
ሁሉ ፡ በመሥዋዕቱ ፡ ዘንድ ፡ ቆመው ፡ ነበር ።
፯ ምሳሌውንም ፡ ይመስል ፡ ጀመር ፥ እንዲህም ፡
አለ ፡—

ባላቅ ፡ ከአራም ፡ አመጣኝ ፥
የሞዓብ ፡ ንጉሥ ፡ ከምሥራቅ ፡ ተራሮች ፤
ና ፥ ያዕቆብን ፡ ርገምልኝ ፤
ና ፥ እስራኤልን ፡ ተጣላልኝ ፡ ብሎ ።
፰ እግዚአብሔር ፡ ያልረገመውን ፡ እንዴት ፡
እረግማለሁ ?
እግዚአብሔርስ ፡ ያልተጣላውን ፡ እንዴት ፡
እጣላለሁ ?
፱ በአምቦች ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ሆኜ ፡ አየዋለሁ ፥
በኮረብቶችም ፡ ላይ ፡ ሆኜ ፡ እመለከተዋለሁ ፤
እነሆ ፥ ብቻውን ፡ የሚቀመጥ ፡ ሕዝብ ፡
ነው ፥
በአሕዛብም ፡ መካከል ፡ አይቈጠርም ።
፲ የያዕቆብን ፡ ትቢያ ፡ ማን ፡ ይቈጥራል ?
የእስራኤልስ ፡ እርቦ ፡ ማን ፡ ይቈጥራል ?
የጻድቃንን ፡ ሞት ፡ እኔ ፡ ልሙት ፥
ፍጻሜዬም ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ፍጻሜ ፡ ትሁን ።

፲፩ ባላቅም ፡ በለዓምን ፡— ያደረግህብኝ ፡ ምንድር ፡
ነው ? ጠላቶቼን ፡ ትረግምልኝ ፡ ዘንድ ፡ ጠራ
ሁህ ፤ እነሆም ፥ ፈጽመህ ፡ ባረክሃቸው ፡ አለው ።
፲፪ እርሱም ፡ መልሶ ፡— በውኑ ፡ እግዚአብሔር ፡
በአፌ ፡ ያደረገውን ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ አልጠነ
ቀቅምን ? አለው ።
፲፫ ባላቅም ፡— በዚያ ፡ ሆነህ ፡ታያቸው ፡ ዘንድ ፥
እባክህ ፥ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ቦታ ፡ ና ፡ ዳር
ቻቸውንም ፡ ብቻ ፡ ታያለህ ፥ ሁሉን ፡ ግን ፡
አታይም ፤ በዚያም ፡ ሆነህ ፡ እነርሱን ፡ ርገም
፲፬ ልኝ ፡ አለው ። ወደ ፡ ጾፊምም ፡ ሜዳ ፡ ወደ ፡
ፈስጋ ፡ ተራራ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ወሰደው ፤ ሰባትም ፡
መሠዊያዎች ፡ ሠራ ፥ በየመሠዊያውም ፡ ላይ ፡
አንድ ፡ ወይፈን ፡ አንድም ፡ አውራ ፡ በግ ፡ አሳ
፲፭ ረገ ። ባላቅንም ፡— እኔ ፡ ወደዚያ ፡ ለመገናኘት ፡
ስሄድ ፡ በዚህ ፡ በመሥዋዕትህ ፡ ዘንድ ፡ ቆይ ፡
፲፮ አለው ። እግዚአብሔርም ፡ በለዓምን ፡ ተገናኘ ፥
ቃልንም ፡ በአፉ ፡ አድርጎ ፡— ወደ ፡ ባላቅ ፡ ተመ
፲፯ ለስ ፥ እንዲህም ፡ በል ፡ አለው ። ወደ ፡ እርሱም ፡
መጣ ፥ እነሆም ፥ እርሱ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የሞ
ዓብ ፡ አለቆች ፡ በመሥዋዕቱ ፡ ዘንድ ፡ ቆመው ፡
ነበር ፤ ባላቅም ፡— እግዚአብሔር ፡ የተናገረው ፡
፲፰ ምንድር ፡ ነው ? አለው ። ምሳሌውንም ፡ ይመ
ስል ፡ ጀመር ፥ እንዲህም ፡ አለ ፡—

ባላቅ ፡ ሆይ ፥ ተነሣ ፥ ስማ ፤
የሴፎር ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ አድምጠኝ ፤
፲፱ ሐሰትን ፡ ይናገር ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡
ሰው ፡ አይደለም ፥
ይጸጸትም ፡ ዘንድ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ አይደ
ለም ።
እርሱ ፡ ያለውን ፡ አያደርገውምን ?
የተናገረውንስ ፡ አይፈጽመውምን ?
፳ እነሆ ፥ ለመባረክ ፡ ትእዛዝን ፡ ተቀብያለሁ ፤
እርሱ ፡ ባርኮአል ፥ እመልሰውም ፡ ዘንድ ፡
አልችልም ።
፳፩ በያዕቆብ ፡ ላይ ፡ ክፋትን ፡ አልተመለከተም ፥
በእስራኤልም ፡ ጠማምነትን ፡ አላየም ፤
አምላኩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
ነው ፥
የንጉሥም ፡ እልልታ ፡ በመካከላቸው ፡ አለ ።
፳፪ እግዚአብሔር ፡ ከግብፅ ፡ አውጥቶአቸዋል ፤
ጕልበቱ ፡ አንድ ፡ ቀንድ ፡ እንዳለው ፡ ነው ።
፳፫ በያዕቆብ ፡ ላይ ፡ አስማት ፡ የለም ፥
በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ምዋርት ፡ የለም ፤
በጊዜው ፡ ስለ ፡ ያዕቆብና ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡—
እግዚአብሔር ፡ ምን ፡ አደረገ ! ይባላል ።
፳፬ እነሆ ፥ ሕዝቡ ፡ እንደ ፡ እንስት ፡ አንበሳ ፡
ይቆማል ፥
እንደ ፡ አንበሳም ፡ ይነሣል ፤
ያደነውን ፡ እስኪበላ ፥
የገደለውንም ፡ ደሙን ፡ እስኪጠጣ ፡ አይተ
ኛም ።

፳፭ ባላቅም ፡ በለዓምን ፡— ከቶ ፡ አትርገማቸው ፥
፳፮ ከቶም ፡ አትባርካቸው ፡ አለው ። በለዓምም ፡
መልሶ ፡ ባላቅን ፡— እግዚአብሔር ፡ የተናገረ
ውን ፡ ሁሉ ፡ አደርጋለሁ ፡ ብዬ ፡ አልተናገርሁህ
ምን ? አለው ።

፳፯ ባላቅም ፡ በለዓምን ፡— ና ፥ ወደ ፡ ሌላ ፡ ስፍራ ፡
እወስድሃለሁ ፤ ምናልባት ፡ በዚህ ፡ ሆነህ ፡ እነር
ሱን ፡ ትረግምልኝ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይወ
፳፰ ድዳል ፡ አለው ። ባላቅም ፡ ምድረ ፡ በዳውን ፡
ከላይ ፡ ወደሚመለከተው ፡ ወደ ፡ ፌጎር ፡ ላይ ፡
፳፱ በለዓምን ፡ ወሰደው ። በለዓምም ፡ ባላቅን ፡—
በዚህ ፡ ሰባት ፡ መሠዊያዎች ፡ ሥራልኝ ፥ በዚ
ህም ፡ ሰባት ፡ ወይፈን ፡ ሰባትም ፡ አውራ ፡ በግ ፡
፴ አዘጋጅልኝ ፡ አለው ። ባላቅም ፡ በለዓም ፡ እን
ዳለው ፡ አደረገ ፥ በየመሠዊያውም ፡ ላይ ፡ አንድ ፡
ወይፈንና ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፡ አሳረገ ።

ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ በለዓምም ፡ እግዚአብሔር ፡ እስራኤልን ፡
ይባርክ ፡ ዘንድ ፡ እንዲወድድ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፥ አስ
ቀድሞ ፡ ያደርግ ፡ የነበረውን ፡ አስማት ፡ ይሻ ፡
ዘንድ ፡ አልሄደም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡
፪ በዳ ፡ ፊቱን ፡ አቀና ። በለዓምም ፡ ዓይኑን ፡ አን
ሥቶ ፡ እስራኤል ፡ በየነገዱ ፡ ተቀምጦ ፡ አየ ፤
የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በላዩ ፡ መጣ ።
፫ ምሳሌውን ፡ ይመስል ፡ ጀመር ፥ እንዲህም ፡
አለ ፡—

የቢዖር ፡ ልጅ ፡ በለዓም ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፥
ዓይኖቹ ፡ የተከፈቱለት ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፤
፬ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ የሚሰማ ፥
ሁሉን ፡ የሚችል ፡ የአምላክን ፡ ራእይ ፡
የሚያይ ፥
የወደቀው ፥ ዓይኖቹም ፡ የተከፈቱለት ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፡—
፭ ያዕቆብ ፡ ሆይ ፥ ድንኳኖችህ ፥
እስራኤል ፡ ሆይ ፥ ማደሪያዎችህ ፡ ምንኛ ፡
ያምራሉ !
፮ እንደ ፡ ሸለቆች ፥
በወንዝ ፡ ዳር ፡ እንዳሉ ፡ አትክልቶች ፥
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተከለው ፡ እሬት ፡
በውኃም ፡ ዳር ፡ እንዳሉ ፡ ዝግባዎች ፡ ተዘ
ርግተዋል ።
፯ ከማድጋዎቹ ፡ ውኃ ፡ ይፈስሳል ፥
ዘሩም ፡ በብዙ ፡ ውኆች ፡ ይሆናል ፥
ንጉሡም ፡ ከአጋግ ፡ ይልቅ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡
ይላል ፥
መንግሥቱም ፡ ይከበራል ።
፰ እግዚአብሔርም ፡ ከግብፅ ፡ አውጥቶታል ፤
ጕልበቱ ፡ እንድ ፡ ቀንድ ፡ እንዳለው ፡ ነው ፤
ጠላቶቹን ፡ አሕዛብን ፡ ይበላል ፥
አጥንቶቻቸውንም ፡ ይሰብብራል ፥
በፍላጻቹም ፡ ይወጋቸዋል ።
፱ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ዐርፎ ፡ ተኝቶአል ፥
እንደ ፡ እንስቴቱም ፡ አንበሳ ፡ ተጋድሞ
አል ፤
ማን ፡ ያስነሣዋል ?
የሚመርቅህ ፡ ሁሉ ፡ የተመረቀ ፡ ይሁን ፥
የሚረግምህም ፡ ሁሉ ፡ የተረገመ ፡ ይሁን ።

፲ የባላቅም ፡ ቍጣ ፡ በበለዓም ፡ ላይ ፡ ነደደ ፤
እጆቹንም ፡ አጨበጨበ ፤ ባላቅም ፡ በለዓምን ፡—
ጠላቶቼን ፡ ትረግም ፡ ዘንድ ፡ ጠራሁህ ፥ እነ
ሆም ፥ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ፈጽመህ ፡ መረቅሃቸው ፤
፲፩ አሁንም ፡ እንግዲህ ፡ ወደ ፡ ስፍራህ ፡ ሽሽ ፤ እኔ ፡
አከብርህ ፡ ዘንድ ፡ ወድጄ ፡ ነበር ፤ እግዚአብ
ሔር ፡ ግን ፥ እነሆ ፥ ክብርህን ፡ ከለከለ ፡ አለው ።
፲፪፡፲፫ በለዓምም ፡ ባላቅን ፡ አለው ፡— ባላቅ ፡ በቤቱ ፡
የሞላውን ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ ቢሰጠኝ ፥ መልካ
ሙን ፡ ወይም ፡ ክፉውን ፡ ከልቤ ፡ ለማድረግ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ እተላለፍ ፡ ዘንድ ፡
አይቻለኝም ፤ እግዚአብሔር ፡ የተናገረውን ፡
እርሱን ፡ እናገራለሁ ፡ ብዬ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ለላክ
ሃቸው ፡ መልእክተኞችህ ፡ አልተናገርኋቸው
፲፬ ምን ? አሁንም ፥ እነሆ ፥ ወደ ፡ ሕዝቤ ፡ እሄዳ
ለሁ ፤ ና ፥ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ በኋለኛው ፡ ዘመን ፡
በሕዝብህ ፡ ላይ ፡ የሚያደርገውን ፡ እነግርሃለሁ ።
፲፭ ምሳሌውንም ፡ ይመስል ፡ ጀመር ፥ እንዲህም ፡
አለ ፡—

የቢዖር ፡ ልጅ ፡ በለዓም ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፥
ዓይኖቹ ፡ የተከፈቱለት ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፤
፲፮ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ የሚሰማ ፥
የልዑልንም ፡ እውቀት ፡ የሚያውቅ ፥
ሁሉን ፡ የሚችል ፡ የአምላክን ፡ ራእይ ፡
የሚያይ ፥
የወደቀው ፥ ዓይኖቹም ፡ የተከፈቱለት ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡—
፲፯ አየዋለሁ ፥ አሁን ፡ ግን ፡ አይደለም ፤
እመለከተዋለሁ ፥ በቅርብ ፡ ግን ፡ አይደ
ለም ፤
ከያዕቆብ ፡ ኮከብ ፡ ይወጣል ፥
ከእስራኤል ፡ በትር ፡ ይነሣል ፥
የሞዓብንም ፡ ማዕዘኖች ፡ ይመታል ፥
የሤትንም ፡ ልጆች ፡ ያጠፋል ።
፲፰ ኤዶምያስም ፡ ርስቱ ፡ ይሆናል ፥
ጠላቱ ፡ ሴይር ፡ ደግሞ ፡ ርስቱ ፡ ይሆናል ፤
እስራኤልም ፡ በኃይል ፡ ያደርጋል ።
፲፱ ከያዕቆብም ፡ የሚወጣ ፡ ገዥ ፡ ይሆናል ፥
ከከተማውም ፡ የቀሩትን ፡ ያጠፋል ።

፳ አማሌቅንም ፡ አይቶ ፡ ምሳሌውን ፡ ይመስል ፡
ጀመር ፥ እንዲህም ፡ አለ ፡—

አማሌቅ ፡ የአሕዛብ ፡ አለቃ ፡ ነበረ ፤
ፍጻሜው ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ ይመጣል ።

፳፩ ቄናውያንንም ፡ አይቶ ፡ ምሳሌውን ፡ ይመ
ስል ፡ ጀመር ፥ እንዲህም ፡ አለ ፡—

ማደሪያህ ፡ የጸና ፡ ነው ፥
ጎጆህም ፡ በአምባ ፡ ላይ ፡ ተሠርቶአል ፤
፳፪ ነገር ፡ ግን ፡ አሦር ፡ እስኪማርክህ ፡ ድረስ ፡

ቁናዊው ፡ ለጥፋት ፡ ይሆናል ።

፳፫ ምሳሌውንም ፡ ይመስል ፡ ጀመር ፥ እንዲህም ፡ አለ ፡—

እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ሲያደርግ ፡
አወይ ! ማን ፡ በሕይወት ፡ ይኖራል ?
፳፬ ከኪቲም ፡ ዳርቻ ፡ መርከቦች ፡ ይመጣሉ ፥
አሦርንም ፡ ያስጨንቃሉ ፥
ዔቦርንም ፡ ያስጨንቃሉ !
እርሱም ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ ይመጣል ።

፳፭ በለዓምም ፡ ተነሣ ፥ ተመልሶም ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ሄደ ፤ ባላቅም ፡ ደግሞ ፡ መንገዱን ፡ ሄደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

፩ እስራኤልም ፡ በሰጢም ፡ ተቀመጡ ፤ ሕዝቡም ፡ ከሞዓብ ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ ያመነዝሩ ፡ ጀመር ። ፪ ሕዝቡንም ፡ ወደ ፡ አምላኮቻቸው ፡ መሥዋዕት ፡ ጠሩ ፤ ሕዝቡም ፡ በሉ ፥ ወደ ፡ አምላኮቻቸውም ፡ ሰገዱ ። ፫ እስራኤልም ፡ ብዔልፌጎርን ፡ ተከተለ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ነደደ ። ፬ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— የእግዚአብሔር ፡ የቍጣው ፡ ጽናት ፡ ከእስራኤል ፡ እንዲመለስ ፡ የሕዝቡን ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ወስደህ ፡ በፀሐዩ ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስቀላቸው ፡ አለው ። ፭ ሙሴም ፡ የእስራኤልን ፡ ዳኞች ፡— እናንተ ፡ ሁሉ ፡ ብዔልፌጎርን ፡ የተከተሉትን ፡ ሰዎቻችሁን ፡ ግደሉ ፡ አላቸው ።

፮ እነሆም ፥ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ አንዱ ፡ መጥቶ ፡ በሙሴና ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ምድያማዊቱን ፡ አንዲቱን ፡ ሴት ፡ ወደ ፡ ወንድሞቹ ፡ አመጣት ፤ እነርሱም ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ ያለቅሱ ፡ ነበር ። ፯ የካህኑም ፡ የአሮን ፡ ልጅ ፡ የአልዓዛር ፡ ልጅ ፡ ፊንሐስ ፡ በየው ፡ ጊዜ ፡ ከማኅበሩ ፡ መካከል ፡ ተነሥቶ ፡ ፰ በእጁ ፡ ጦር ፡ አነሣ ፤ ያንንም ፡ የእስራኤልን ፡ ሰው ፡ ተከትሎ ፡ ወደ ፡ ድንኳኑ ፡ ገባ ። እስራኤላዊውንም ፡ ሰውና ፡ ሴቲቱን ፡ ሁለቱን ፡ ሆዳቸውን ፡ ወጋቸው ። ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ መቅሠፍቱ ፡ ተከለከለ ። ፱ በመቅሠፍትም ፡ የሞተው ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ነበረ ።

፲ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ፲፩ የካህኑ ፡ የአሮን ፡ ልጅ ፡ የአልዓዛር ፡ ልጅ ፡ ፊንሐስ ፡ በቅንዓቴ ፡ በመካከላቸው ፡ ቀንቶአልና ፡ ቍጣዬን ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መለሰ ፤ እኔም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ በቅንዓቴ ፡ አላጠፋሁም ። ፲፪ ስለዚህ ፥ እነሆ ፥ የሰላሜን ፡ ቃል ፡ ፲፫ ኪዳን ፡ እሰጠዋለሁ ። ለአምላኩም ፡ ቀንቶአልና ፥ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ አስተሰርዮአልና ፡ ለእርሱ ፡ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ለዘሩ ፡ ለዘላለም ፡ ክህነት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ይሆንለታል ።

፲፬ ከምድያማዊቱም ፡ ጋር ፡ የተገደለው ፡ የእስራኤላዊው ፡ ሰው ፡ ስም ፡ ዘንበሪ ፡ ነበረ ፤ የአባቱ ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ የስምዖናውያን ፡ የሆነ ፡ የሰሉ ፡ ፲፭ ልጅ ፡ ነበረ ። የተገደለችውም ፡ ምድያማዊት ፡ ስምዋ ፡ ከስቢ ፡ ነበረ ፤ እርስዋም ፡ የሱር ፡ ልጅ ፡ ነበረች ፤ እርሱም ፡ በምድያም ፡ ዘንድ ፡ የአባቱ ፡ ቤት ፡ ወገን ፡ አለቃ ፡ ነበረ ።

፲፮ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ፲፯፣፲፰ በፌጎር ፡ በመቅሠፍቱ ፡ ቀን ፡ ስለ ፡ ተገደለችው ፡ ስለ ፡ ምድያም ፡ አለቃ ፡ ልጅ ፡ ስለ ፡ እኅታቸው ፡ ስለ ፡ ከስቢ ፡ በፌጎር ፡ ምክንያት ፡ በሸነገሉአችሁ ፡ ሽንገላ ፡ አስጨንቀዋችኋልና ፡ ምድያማውያንን ፡ አስጨንቁአቸው ፡ ግደሉአቸውም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ መቅሠፍቱ ፡ ከሆነ ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሙሴንና ፡ የካህኑን ፡ የአሮን ፡ ልጅ ፡ አልዓዛርን ፡— ፪ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያለውን ፥ በእስራኤል ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወጣውን ፡ ሁሉ ፥ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ በየአባቶቻቸው ፡ ቤት ፡ ቍጠሩ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ። ፫ ሙሴና ፡ ካህኑ ፡ አልዓዛር ፡ በዮርዳኖስ ፡ አጠገብ ፡ በኢያሪኮ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በሞዓብ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡— ፬ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ ከግብፅም ፡ ምድር ፡ የወጡትን ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እንዳዘዛቸው ፥ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያለውን ፡ ሕዝቡን ፡ ቍጠሩ ፡ ብለው ፡ ተናገሩአቸው ።

፭ የእስራኤል ፡ በኵር ፡ ሮቤል ፤ የሮቤል ፡ ልጆች ፤ ከሄኖኅ ፡ የሄኖኃውያን ፡ ወገን ፥ ከፈሉስ ፡ የፈሉሳውያን ፡ ወገን ፥ ፮ ከአስሮን ፡ የአስሮናውያን ፡ ወገን ፥ ከከርሚ ፡ የከርማውያን ፡ ወገን ። ፯ እነዚህ ፡ የሮቤላውያን ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ፤ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩት ፡ አርባ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ነበሩ ። ፰ የፈሉስም ፡ ልጆች ፤ ኤልያብ ። ፱ የኤልያብም ፡ ልጆች ፤ ነሙኤል ፥ ዳታን ፥ አቤሮን ፤ እነዚህ ፡ ዳታንና ፡ አቤሮን ፡ ከማኅበሩ ፡ የተመረጡ ፡ ነበሩ ፤ ከቆሬ ፡ ወገን ፡ ጋር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ በመፀ ፡ ጊዜ ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ ተጣሉ ፤ ፲ ያም ፡ ወገን ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ ምድሪቱ ፡ አፍዋን ፡ ከፍታ ፡ ከቆሬ ፡ ጋር ፡ ዋጠቻቸው ፤ በዚያም ፡ ጊዜ ፡ እሳቲቱ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳውን ፡ ሰዎች ፡ አቃጠለቻቸው ፤ እነርሱም ፡ ለምልክት ፡ ሆኑ ። ፲፩ የቆሬ ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ አልሞቱም ።

፲፪ የስምዖን ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፤ ከነሙኤል ፡ የነሙኤላውያን ፡ ወገን ፥ ከያሚን ፡ የያሚናውያን ፡ ወገን ፥ ከያኪን ፡ የያኪናውያን ፡ ወገን ፥ ፲፫ ከዛራ ፡ የዛራውያን ፡ ወገን ፥ ከሳኡል ፡ የሳኡላውያን ፡ ወገን ። ፲፬ እነዚህ ፡ የስምዖናውያን ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ፤ ሀያ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፲፭ የጋድ ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፤ ከጽፎን ፡ የጽፎናውያን ፡ ወገን ፥ ከሐጊ ፡ የሐጋውያን ፡ ወገን ፥ ከሹኒ ፡ የሹናውያን ፡ ወገን ፥ ፲፮ ከኤስናን ፡ የኤስናናውያን ፡ ወገን ፥ ከዔሪ ፡ የዔራውያን ፡ ወገን ፥ ፲፯ ከአሮድ ፡ የአሮዳውያን ፡ ወገን ፥ ከአር

፲፰ ኤሊ ፡ የአርኤላውያን ፡ ወገን ። እነዚህ ፡ የጋድ ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ፤ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩት ፡ አርባ ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፲፱ የይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ዔርና ፡ አውናን ፤ ዔርና ፡ ፳ አውናንም ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ሞቱ ። የይሁዳም ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፤ ከሴሎም ፡ የሴሎማውያን ፡ ወገን ÷ ከፋሬስ ፡ የፋሬሳውያን ፡ ፳፩ ወገን ÷ ከዛራ ፡ የዛራውያን ፡ ወገን ። የፋሬስም ፡ ልጆች ፤ ከኤስሮም ፡ የኤስሮማውያን ፡ ወገን ÷ ፳፪ ከሐሙል ፡ የሐሙላውያን ፡ ወገን ። እነዚህ ፡ የይሁዳ ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ፤ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩት ፡ ሰባ ፡ ስድስት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፳፫ የይሳኮር ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፤ ከቶላ ፡ የቶላውያን ፡ ወገን ÷ ከፋዋ ፡ የፋዋውያን ፡ ወገን ÷ ፳፬ ከያሱብ ፡ የያሱባውያን ፡ ወገን ÷ ከሺምሮን ፡ ፳፭ የሺምሮናውያን ፡ ወገን ። እነዚህ ፡ የይሳኮር ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ፤ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩት ፡ ስድሳ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፳፮ የዛብሎን ፡ ወገኖች ፡ በየወገናቸው ፤ ከሴሬድ ፡ የሴሬዳውያን ፡ ወገን ÷ ከኤሎን ፡ የኤሎናውያን ፡ ወገን ÷ ከያሕልኤል ፡ የያሕልኤላውያን ፡ ፳፯ ወገን ። እነዚህ ፡ የዛብሎናውያን ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ፤ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩት ፡ ስድሳ ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፳፰ የዮሴፍ ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፤ ምናሴና ፡ ፳፱ ኤፍሬም ። የምናሴ ፡ ልጆች ፤ ከማኪር ፡ የማኪራውያን ፡ ወገን ፤ ማኪርም ፡ ገለዓድን ፡ ወለደ ፤ ፴ ከገለዓድ ፡ የገለዓዳውያን ፡ ወገን ። የገለዓድ ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ከኢዔዝር ፡ የኢዔዝራውያን ፡ ወገን ÷ ከኬሌግ ፡ የኬሌጋውያን ፡ ፴፩ ወገን ÷ ከአሥሬኤል ፡ የአሥሬኤላውያን ፡ ወገን ÷ ፴፪ ከሴኬም ፡ የሴኬማውያን ፡ ወገን ÷ ከሸሚዳ ፡ የሸሚዳውያን ፡ ወገን ÷ ከኦፌር ፡ የኦፌራውያን ፡ ፴፫ ወገን ። የኦፌርም ፡ ልጅ ፡ ሰለጰዓድ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ እንጂ ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ አልነበሩትም ፤ የሰለጰዓድም ፡ የሴቶች ፡ ልጆቹ ፡ ስም ፡ ማህለህ ÷ ኑዓ ÷ ዔግላ ÷ ሚልካ ÷ ቲርጻ ፡ ፴፬ ነበረ ። እነዚህ ፡ የምናሴ ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ፤ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩት ፡ አምሳ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፴፭ በየወገናቸው ፡ የኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ከሱቱላ ፡ የሱቱላውያን ፡ ወገን ÷ ከቤኬር ፡ የቤኬራውያን ፡ ወገን ÷ ከታሐን ፡ የታሐ ፴፮ ናውያን ፡ ወገን ። እነዚህ ፡ የሱቱላ ፡ ልጆች ፡ ፴፯ ናቸው ፤ ከዔዴን ፡ የዔዴናውያን ፡ ወገን ። እነዚህ ፡ የኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ፤ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩት ፡ ሠላሳ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። በየወገናቸው ፡ የዮሴፍ ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።

፴፰ የብንያም ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፤ ከቤላ ፡ የቤላውያን ፡ ወገን ÷ ከአስቤል ፡ የአስቤላውያን ፡ ወገን ÷ ከአኪራን ፡ የአኪራናውያን ፡ ወገን ÷ ፴፱ ከሶፋን ፡ የሶፋናውያን ፡ ወገን ÷ ከሑፋም ፡ የሑፋማውያን ፡ ወገን ። ፵ የቤላም ፡ ልጆች ፤ አርድና ፡ ናዕማን ፤ ከአርድ ፡ የአርዳውያን ፡ ወገን ÷ ከናዕማን ፡ የናዕማናውያን ፡ ወገን ። ፵፩ በየወገናቸው ፡ የብንያም ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩት ፡ አርባ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፵፪ በየወገናቸው ፡ የዳን ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ከሰምዔ ፡ የሰምዔያውያን ፡ ወገን ፤ በየወገናቸው ፡ የዳን ፡ ወገኖች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። ፵፫ የሰምዔያውያን ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ ከእነርሱ ፡ እንደ ፡ ተቈጠሩ ፡ ስድሳ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፵፬ የአሴር ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፤ ከዩምና ፡ የዩምናውያን ፡ ወገን ÷ ከየሱዋ ፡ የየሱዋውያን ፡ ወገን ÷ ከበሪዓ ፡ የበሪዓውያን ፡ ወገን ። ፵፭ ከበሪዓ ፡ ልጆች ፤ ከሔቤር ፡ የሔቤራውያን ፡ ወገን ÷ ከመልኪኤል ፡ የመልኪኤላውያን ፡ ፵፮ ወገን ። የአሴርም ፡ የሴት ፡ ልጁ ፡ ስም ፡ ሤራሕ ፡ ፵፯ ነበረ ። እነዚህ ፡ የአሴር ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ፤ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩት ፡ አምሳ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፵፰ የንፍታሌም ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፤ ከያሕጽኤል ፡ የያሕጽኤላውያን ፡ ወገን ÷ ከጉኒ ፡ ፵፱ የጉናውያን ፡ ወገን ÷ ከዬጽር ፡ የዬጽራውያን ፡ ፶ ወገን ÷ ከሺሌም ፡ የሺሌማውያን ፡ ወገን ። በየወገናቸው ፡ የንፍታሌም ፡ ወገኖች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ከእነርሱም ፡ የተቈጠሩት ፡ አርባ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፶፩ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የተቈጠሩት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ስድስት ፡ መቶ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ነበሩ ።

፶፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፶፫ ተናገረው ፦ ለእነዚህ ፡ በየስማቸው ፡ ቍጥር ፡ ፶፬ ምድሪቱ ፡ ርስት ፡ ሆና ፡ ትከፈላለች ። ለብዙዎቹ ፡ እንደ ፡ ብዛታቸው ÷ ለጥቂቶቹም ፡ እንደ ፡ ጥቂትነታቸው ፡ መጠን ፡ ርስትን ፡ ትሰጣቸዋለህ ። ለሁሉ ፡ እንደ ፡ ቍጥራቸው ፡ መጠን ፡ ፶፭ ርስታቸው ፡ ይሰጣቸዋል ። ነገር ፡ ግን ፡ ምድሪቱ ፡ በዕጣ ፡ ትከፈላለች ፤ እንደ ፡ አባቶቻቸው ፡ ፶፮ ነገድ ፡ ስም ፡ ይወርሳሉ ። በብዙዎችና ፡ በጥቂቶች ፡ መካከል ፡ ርስታቸው ፡ በዕጣ ፡ ትከፈላለች ።

፶፯ ከሌዋውያንም ፡ በየወገናቸው ፡ የተቈጠሩት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ከጌድሶን ፡ የጌድሶናውያን ፡ ወገን ÷ ከቀዓት ፡ የቀዓታውያን ፡ ወገን ÷ ከሜራሪ ፡ ፶፰ የሜራራውያን ፡ ወገን ። እነዚህ ፡ የሌዊ ፡ ወገኖች ፡ ናቸው ፤ የሊብናውያን ፡ ወገን ÷ የኬብሮናውያን ፡ ወገን ÷ የሞሖላውያን ፡ ወገን ÷ የሙሳውያን ፡ ወገን ÷ የቆሬያውያን ፡ ወገን ። ቀዓትም ፡ እንበረምን ፡ ወለደ ። ፶፱ የእንበረም ፡ ሚስት ፡ ስም ፡ ዮካብድ ፡ ነበረ ። እርስዋ ፡ በግብፅ ፡ ከሌዊ ፡ የተወለደች ፡ የሌዊ ፡ ልጅ ፡ ነበረች ፤ ለእንበረምም ፡ አሮንንና ፡ ሙሴን ፡ እኅታቸውንም ፡ ማርያምን ፡ ወለደችለት ። ፷ ለአሮንም ፡ ናዳብ ÷ አብዩድ ÷ አልዓዛር ÷ ኢታምር ፡ ተወለዱለት ።

፷፩ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ሌላ ፡ እሳት ፡ በቀረቡ ፡ ጊዜ ፡ ናዳብና ፡ አብዩድ ፡ ሞቱ ። ፷፪ ከአንድ ፡ ወርም ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያሉ ፡ ወንዶች ፡ ሁሉ ፡ ከእነርሱ ፡ የተቈጠሩ ፡ ሀያ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ነበሩ ። ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ርስት ፡ አልተሰጣቸውምና ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ አልተቈጠሩም ።

፷፫ በሞዓብ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ በዮርዳኖስ ፡ አጠገብ ፡ በኢያሪኮ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ሲቈጥሩ ÷ ሙሴና ፡ ካህኑ ፡ አልዓዛር ፡ የቈጠሩአቸው ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። ፷፬ ነገር ፡ ግን ፡ ሙሴና ፡ ካህኑ ፡ አሮን ፡ በሲና ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ በቈጠሩአቸው ፡ ጊዜ ፡ ከነበሩት ፡ ከእነዚያ ፡ መካከል ፡ አንድም ፡ ሰው ፡ አልነበረም ። ፷፭ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡— በእውነት ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ይሞታሉ ፡ ብሎ ፡ ተናግሮአልና ። ከዮፎኒ ፡ ልጅ ፡ ከካሌብ ፡ ከነዌም ፡ ልጅ ፡ ከኢያሱ ፡ በቀር ፡ ከእነርሱ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ስንኳ ፡ አልቀረም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

፩ ከዮሴፍ ፡ ልጅ ፡ ከምናሴ ፡ ወገኖች ÷ የምናሴ ፡ ልጅ ፡ የማኪር ፡ ልጅ ፡ የገለዓድ ፡ ልጅ ፡ የኦፌር ፡ ልጅ ፡ የሰለጰዓድ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ቀረቡ ፤ የእነዚህም ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ስም ፡ ማህለህ ÷ ኑዓ ÷ ዔግላ ÷ ሚልካ ÷ ቲርጻ ፡ ነበረ ። ፪ በመገናኛውም ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ አጠገብ ፡ በሙሴና ፡ በካህኑ ፡ በአልዓዛር ፡ በአለቆቹም ፡ በማኅበሩም ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ቆመው ፡— ፫ አባታችን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ሞተ ፤ በራሱ ፡ ኀጢአት ፡ ሞተ ፡ እንጂ ፡ ከቆሬ ፡ ጋር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ወገን ፡ መካከል ፡ አልነበረም ፤ ወንዶችም ፡ ልጆች ፡ አልነበሩትም ። ፬ ወንድ ፡ ልጅስ ፡ ባይኖረው ፡ የአባታችን ፡ ስም ፡ ከወገኑ ፡ መካከል ፡ ለምን ፡ ይጠፋል ? በአባታችን ፡ ወንድሞች ፡ መካከል ፡ ርስትን ፡ ስጠን ፡ አሉ ። ፭ ሙሴም ፡ ነገራቸውን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አቀረበ ።

፮ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ፯ የሰለጰዓድ ፡ ልጆች ፡ እውነት ፡ ተናግረዋል ፤ በአባታቸው ፡ ወንድሞች ፡ መካከል ፡ የርስት ፡ ድርሻ ፡ ስጣቸው ፤ የአባታቸውን ፡ ርስት ፡ ለእነርሱ ፡ አሳልፈህ ፡ ስጥ ። ፰ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— ሰው ፡ ቢሞት ፡ ወንድ ፡ ልጅም ፡ ባይኖረው ÷ ርስቱ ፡ ለሴት ፡ ልጁ ፡ ይለፍ ፤ ፱ ሴት ፡ ልጅም ፡ ባትኖረው ፡ ርስቱን ፡ ለወንድሞቹ ፡ ስጡ ፤ ፲ ወንድሞችም ፡ ባይኖሩት ፡ ርስቱን ፡ ለአባቱ ፡ ወንድሞች ፡ ስጡ ፤ ፲፩ የአባቱም ፡ ወንድሞች ፡ ባይኖሩት ፡ ከወገኑ ፡ ለቀረበ ፡ ዘመድ ፡ ርስቱን ፡ ስጡ ፡ እርሱም ፡ ይውረሰው ፤ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ ይሁን ።

፲፪ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— ወደ ፡ ዚህ ፡ ወደ ፡ ዓባሪም ፡ ተራራ ፡ ውጣ ÷ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ የሰጠኋትን ፡ ምድር ፡ እይ ፤ ፲፫ ባየሃትም ፡ ጊዜ ፡ ወንድምህ ፡ አሮን ፡ እንደ ፡ ተከማቸ ፡ አንተ ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ ወገንህ ፡ ትከማቻለህ ። ፲፬ እናንተ ፡ በጺን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በማኅበሩ ፡ ጠብ ፡ በቃሌ ፡ ላይ ፡ ዐምፃችኋልና ÷ በእነርሱም ፡ ፊት ፡ በውኃው ፡ ዘንድ ፡ አልቀደሳችሁኝምና ። ይህም ፡ በጺን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በቃዴስ ፡ ያለው ፡ የመሪባ ፡ ውኃ ፡ ነው ።

፲፭ ሙሴም ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ፲፮፲፯ የእግዚአብሔር ፡ ማኅበር ፡ እረኛ ፡ እንደሌለው ፡ መንጋ ፡ እንዳይሆን ÷ በፊታቸው ፡ የሚወጣውን ፡ በፊታቸውም ፡ የሚገባውን ፡ የሚያስወጣቸውንም ፡ የሚያስገባቸውንም ፡ ሰው ፡ የሥጋ ፡ ሁሉ ፡ መንፈስ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ በማኅበሩ ፡ ላይ ፡ ይሹመው ። ፲፰ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— መንፈስ ፡ ያለበትን ፡ ሰው ፡ የነዌን ፡ ልጅ ፡ ኢያሱን ፡ ወስደህ ፡ እጅህን ፡ በላዩ ፡ ጫንበት ፤ ፲፱ በካህኑ ፡ በአልዓዛርና ፡ በማኅበሩ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ አቁመው ÷ እነርሱም ፡ እያዩ ፡ እዘዘው ። ፳ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ እንዲታዘዙት ፡ ከክብርህ ፡ አኑርበት ። ፳፩ በካህኑም ፡ በአልዓዛር ፡ ፊት ፡ ይቁም ፤ እርሱም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በኡሪም ፡ ፍርድ ፡ ይጠይቅለት ፤ እርሱ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ በቃሉ ፡ ይውጡ ÷ በቃሉም ፡ ይግቡ ። ፳፪ ሙሴም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ አደረገ ፤ ኢያሱንም ፡ ወስዶ ፡ በካህኑ ፡ በአልዓዛርና ፡ በማኅበሩ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ አቆመው ፤ ፳፫ እግዚአብሔርም ፡ በሙሴ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ÷ እጁን ፡ በላዩ ፡ ጫነበት ÷ አዘዘውም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ፪ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ እዘዛቸው ፡— መብሌን ÷ ለእኔ ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ በእሳት ፡ የተደረገውን ፡ ቍርባኔን ÷ መባዬን ፡ በየጊዜው ፡ ታቀርቡልኝ ፡ ዘንድ ፡ ጠብቁ ። ፫ እንዲህም ፡ በላቸው ፡— በእሳት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የምታቀርቡት ፡ ቍርባን ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ለዘወትር ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ነውር ፡ የሌለባቸውን ፡ ሁለት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ታቀርባላችሁ ። ፬ አንዱን ፡ ጠቦት ፡ በማለዳ ÷ ሌላውንም ፡ ጠቦት ፡ በማታ ፡ አቅርብ ፤ ፭ ለእህልም ፡ ቍርባን ፡ የኢን ፡ መስፈሪያ ፡ አራተኛ ፡ እጅ ፡ በሆነ ፡ ተወቅጦ ፡ በተጠለለ ፡ ዘይት ፡ የተለወሰ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ አሥረኛ ፡ እጅ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ ታቀርባለህ ። ፮ በእሳት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ የቀረበ ፡ በሲና ፡ ተራራ ፡ የተሠራ ፡ ለዘወትር ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ነው ። ፯ የመጠጡ ፡ ቍርባን ፡ ለአንድ ፡ ጠቦት ፡ የኢን ፡ መስፈሪያ ፡ አራ

ተኛው ፡ እጅ ፡ ነው ፤ በመቅደሱ ፡ ውስጥ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለመጠጥ ፡ ቍርባን ፡ መጠጥ ፡ ታፈስስለህ ። ፰ ሌላውንም ፡ ጠቦት ፡ በማታ ፡ ጊዜ ፡ ታቀርበለህ ፤ የእህሉን ፡ ቍርባንና ፡ የመጠጡን ፡ ቍርባን ፡ በማለዳ ፡ እንዳቀረብህ ፡ በእሳት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ ታቀርበዋለህ ።

፱ በሰንበትም ፡ ቀን ፡ ነውር ፡ የሌለባቸውን ፡ ሁለት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፥ ለእህልም ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሁለት ፡ እጅ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፥ የመጠጡንም ፡ ቍርባን ፡ ታቀርባላችሁ ። ፲ በዘወትር ፡ ከሚቃጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ ሌላ ፥ ከመጠጡም ፡ ቍርባን ፡ ሌላ ፥ በየሰንበቱ ፡ ሁሉ ፡ የምታቀርቡት ፡ የሚቃጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ ይህ ፡ ነው ።

፲፩ በወሩም ፡ መባቻ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ታቀርባላችሁ ፤ ሁለት ፡ ወይፈን ፥ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፥ ነውርም ፡ የሌለባቸውን ፡ ሰባት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፥ ፲፪ ለእያንዳንዱም ፡ ወይፈን ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሦስት ፡ እጅ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፥ ለአውራው ፡ በግም ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሁለት ፡ እጅ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፥ ፲፫ ለእያንዳንዱም ፡ ጠቦት ፡ ለእህል ፡ ቍርባን ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ ከመስፈሪያው ፡ አሥረኛ ፡ እጅ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፥ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ በእሳት ፡ ታቀርባላችሁ ። ፲፬ የመጠጥ ፡ ቍርባናቸውም ፡ ለአንድ ፡ ወይፈን ፡ የኢን ፡ ግማሽ ፥ ለአውራው ፡ በግም ፡ የኢን ፡ ሢሶ ፥ ለአንዱም ፡ ጠቦት ፡ የኢን ፡ አራተኛ ፡ እጅ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ይሆናል ፤ ይህ ፡ ለዓመቱ ፡ የወር ፡ መባቻ ፡ ሁሉ ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ነው ። ፲፭ ለእግዚአብሔርም ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፡ ታቀርባላችሁ ፤ በዘወትር ፡ ከሚቃጠለው ፡ መሥዋዕትና ፡ ከመጠጡ ፡ ቍርባን ፡ ሌላ ፡ ይቀርባል ።

፲፮ በመጀመሪያው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፋሲካ ፡ ነው ። ፲፯ ከዚህም ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ አምስተኛው ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ ይሆናል ፤ ሰባት ፡ ቀን ፡ ቂጣ ፡ እንጀራ ፡ ትበላላችሁ ። ፲፰ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ይሆናል ፤ በእርሱም ፡ የተግባርን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አትሥሩበት ። ፲፱ በእሳትም ፡ የተደረገውን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ታቀርባላችሁ ፤ ሁለት ፡ ወይፈኖች ፥ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፥ ሰባት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፤ ነውር ፡ የሌለባቸው ፡ ይሁኑላችሁ ። ፳ የእህል ፡ ቍርባናቸውንም ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፥ ለአንድ ፡ ወይፈን ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሦስት ፡ እጅ ፥ ለአውራውም ፡ በግ ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሁለት ፡ እጅ ፥ ፳፩ ለሰባቱም ፡ ጠቦቶች ፡ ለእያንዳንዱ ፡ ጠቦት ፡ ከመስፈሪያው ፡ አሥረኛ ፡ እጅ ፡ ታቀርባላችሁ ። ፳፪ ማስተስረያ ፡ የሚሆንላችሁን ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ታቀርባላችሁ ። ፳፫ ማልዶ ፡ ከሚቀርበው ፡ በዘወትር ፡ ከሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ሌላ ፡ እነዚህን ፡ ታቀርባላችሁ ። ፳፬ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ በእሳት ፡ የሚደረገውን ፡ የቍርባኑን ፡ መብል ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በየዕለቱ ፡ እንዲሁ ፡ ታቀርባላችሁ ፤ በዘወትር ፡ ከሚቃጠለው ፡ መሥዋዕትና ፡ ከመጠጡ ፡ ቍርባን ፡ ሌላ ፡ ይቀርባል ። ፳፭ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ይሁንላችሁ ፤ የተግባርን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አትሥሩበት ።

፳፮ ደግሞ ፡ በበኵራት ፡ ቀን ፡ ከሰባቱ ፡ ሱባዔ ፡ በዓላችሁ ፡ አዲሱን ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ባቀረባችሁ ፡ ጊዜ ፥ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ይሆንላችኋል ፤ የተግባርን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አትሥሩበት ። ፳፯ ለእግዚአብሔርም ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ታቀርባላችሁ ፤ ሁለት ፡ ወይፈኖች ፥ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፥ ሰባት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፥ ፳፰ ለእህል ፡ ቍርባናቸው ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፥ ለእያንዳንዱ ፡ ወይፈን ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሦስት ፡ እጅ ፥ ለአንዱም ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሁለት ፡ እጅ ፥ ፳፱ ለሰባቱም ፡ ጠቦቶች ፡ ለእያንዳንዱ ፡ ጠቦት ፡ ከመስፈሪያው ፡ አሥረኛ ፡ እጅ ፡ ታቀርባላችሁ ። ፴ ማስተስረያ ፡ የሚሆንላችሁን ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ታቀርባላችሁ ። ፴፩ በዘወትር ፡ ከሚቃጠለው ፡ መሥዋዕትና ፡ ከእህሉ ፡ ቍርባን ፡ ሌላ ፡ እነርሱንና ፡ የመጠጥ ፡ ቍርባናቸውን ፡ ታቀርባላችሁ ፤ ነውርም ፡ የሌለባቸው ፡ ይሁኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

፩ በሰባተኛውም ፡ ወር ፡ ከወሩ ፡ በመጀመሪያ ፡ ቀን ፡ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ይሁንላችሁ ፤ የተግባርን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አትሥሩበት ፤ መለከቶች ፡ የሚነፉበት ፡ ቀን ፡ ነው ። ፪ ለእግዚአብሔር ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፥ አንድ ፡ ወይፈን ፥ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፥ ነውር ፡ የሌለባቸውን ፡ ሰባት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፥ ፫ ለእህል ፡ ቍርባናቸው ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፥ ለወይፈኑ ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሦስት ፡ እጅ ፥ ለአውራው ፡ በግ ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሁለት ፡ እጅ ፥ ፬ ለሰባቱ ፡ ጠቦቶች ፡ ለእያንዳንዱ ፡ ከመስፈሪያው ፡ አሥረኛ ፡ እጅ ፡ ታቀርባላችሁ ። ፭ ማስተስረያም ፡ የሚሆንላችሁን ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፡ ለኃ

፮ ጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ታቀርባላችሁ ። በወሩ ፡
መባቻ ፡ ከሚቃጠለው ፡ መሥዋዕትና ፡ ከእህሉ ፡
ቍርባን ፥ በዘወትርም ፡ ከሚቃጠለው ፡ መሥዋ
ዕትና ፡ ከእህሉ ፡ ቍርባን ፥ ከመጠጡም ፡ ቍር
ባን ፡ ሌላ ፥ እንደ ፡ ሕጋቸው ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ በእሳት ፡ የሚቀርቡ ፡
ናቸው ።

፯ ከዚህም ፡ ከሰባተኛው ፡ ወር ፡ በአሥረኛው ፡
ቀን ፡ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ይሁንላችሁ ፤ ሰውነታ
ችሁን ፡ አስጨንቁት ፤ ከሥራ ፡ ሁሉ ፡ ምንም ፡
፰ አታድርጉ ። ለእግዚአብሔርም ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡
እንዲሆን ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፥ አንድ ፡
ወይፈን ፥ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፥ ሰባት ፡ የአንድ ፡
ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ታቀርባላችሁ ፤
፱ ነውር ፡ የሌለባቸውም ፡ ይሁኑ ። ለእህል ፡ ቍር
ባናቸውም ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡ መልክም ፡
ዱቄት ፥ ለወይፈኑ ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡
እጅ ፡ ሦስት ፡ እጅ ፥ ለአውራው ፡ በግ ፡ ከመ
፲ ስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡ ሁለት ፡ እጅ ፥ ለሰ
ባቱ ፡ ጠቦቶች ፡ ለእያንዳንዱ ፡ ከመስፈሪያው ፡
፲፩ አሥረኛ ፡ እጅ ፥ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡
አውራ ፡ ፍየል ፡ አቅርቡ ። ከሚያስተሰርየው ፡
ከኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፥ በዘወትርም ፡ ከሚ
ቃጠለው ፡ መሥዋዕትና ፡ ከእህሉ ፡ ቍርባን ፥
ከመጠጥ ፡ ቍርባናቸውም ፡ ሌላ ፡ አቅርቡት ።

፲፪ ከሰባተኛውም ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ አምስተኛው ፡
ቀን ፡ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ይሁንላችሁ ፤ የተግባ
ርን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አትሥሩበት ፥ ሰባት ፡ ቀንም ፡
፲፫ ለእግዚአብሔር ፡ በዓል ፡ አድርጉ ። ለእግዚአ
ብሔርም ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እንዲሆን ፡ የሚቃ
ጠለውን ፡ መሥዋዕት ፥ አሥራ ፡ ሦስት ፡ ወይ
ፈኖች ፥ ሁለት ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ አሥራ ፡
አራት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦ
ቶች ፡ አቅርቡ ፤ ነውር ፡ የሌለባቸውም ፡ ይሁኑ ።
፲፬ ለእህል ፡ ቍርባናቸውም ፡ በዘይት ፡ የተለወሰ ፡
መልክም ፡ ዱቄት ፥ ለአሥራ ፡ ሦስት ፡ ወይፈ
ኖች ፡ ለእያንዳንዱ ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡
እጅ ፡ ሦስት ፡ እጅ ፥ ለሁለቱ ፡ አውራ ፡ በጎች ፡
ለእያንዳንዱ ፡ ከመስፈሪያው ፡ ከአሥር ፡ እጅ ፡
፲፭ ሁለት ፡ እጅ ፥ ለአሥራ ፡ አራቱ ፡ ጠቦቶች ፡ ለእ
ያንዳንዱ ፡ ከመስፈሪያው ፡ አሥረኛ ፡ እጅ ፥
፲፮ ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡
ፍየል ፡ ታቀርባላችሁ ፤ በዘወትር ፡ ከሚቃጠ
ለው ፡ መሥዋዕትና ፡ ከእህሉ ፡ ቍርባን ፡ ከመ
ጠጡም ፡ ቍርባን ፡ ሌላ ፡ የሚቀርቡ ፡ ናቸው ።

፲፯ በሁለተኛውም ፡ ቀን ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ወይ
ፈኖችን ፥ ሁለት ፡ አውራ ፡ በጎችን ፥ ነውር ፡
የሌለባቸው ፡ አሥራ ፡ አራት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡
፲፰ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶችን ፥ ለወይፈኖቹና ፡ ለአ
ውራ ፡ በጎቹ ፡ ለጠቦቶቹም ፡ የእህል ፡ ቍርባና
ቸውንና ፡ የመጠጥ ፡ ቍርባናቸውን ፡ እንደ ፡
፲፱ ቍጥራቸው ፡ መጠን ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፥ ለኃጢአ
ትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየልን ፡
ታቀርባላችሁ ፤ በዘወትር ፡ ከሚቃጠለው ፡
መሥዋዕትና ፡ ከእህሉ ፡ ቍርባን ፡ ከመጠጡም ፡
ቍርባናቸው ፡ ሌላ ፡ የሚቀርቡ ፡ ናቸው ።

፳ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ አሥራ ፡ አንድ ፡ ወይፈ
ኖች ፥ ሁለት ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ ነውር ፡ የሌለባ
ቸውን ፡ አሥራ ፡ አራት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡
፳፩ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፥ ለወይፈኖቹና ፡ ለአ
ውራ ፡ በጎቹ ፡ ለጠቦቶቹም ፡ የእህል ፡ ቍርባናቸ
ውንና ፡ የመጠጥ ፡ ቍርባናቸውን ፡ እንደ ፡ ቍጥ
፳፪ ራቸው ፡ መጠን ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፥ ለኃጢአትም ፡
መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፥ በዘወ
ትር ፡ ከሚቃጠለው ፡ መሥዋዕትና ፡ ከእህሉ ፡
ቍርባን ፡ ከመጠጡም ፡ ቍርባን ፡ ሌላ ፡ ታቀር
ባላችሁ ።

፳፫ በአራተኛውም ፡ ቀን ፡ አሥር ፡ ወይፈኖች ፥
ሁለት ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ ነውር ፡ የሌለባቸውን ፡
አሥራ ፡ አራት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡
፳፬ ጠቦቶች ፥ ለወይፈኖቹና ፡ ለአውራ ፡ በጎቹ ፡
ለጠቦቶቹም ፡ የእህል ፡ ቍርባናቸውንና ፡ የመ
ጠጥ ፡ ቍርባናቸውን ፡ እንደ ፡ ቍጥራቸውም ፡
፳፭ መጠን ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፥ ለኃጢአትም ፡ መሥዋ
ዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፥ በዘወትር ፡ ከሚ
ቃጠለው ፡ መሥዋዕትና ፡ ከእህሉ ፡ ቍርባን ፡
ከመጠጡም ፡ ቍርባን ፡ ሌላ ፡ ታቀርባላችሁ ።

፳፮ በአምስተኛውም ፡ ቀን ፡ ዘጠኝ ፡ ወይፈኖች ፥
ሁለት ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ ነውር ፡ የሌለባቸውን ፡
አሥራ ፡ አራት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡
፳፯ ጠቦቶች ፥ ለወይፈኖቹና ፡ ለአውራ ፡ በጎቹ ፡
ለጠቦቶቹም ፡ የእህል ፡ ቍርባናቸውንና ፡ የመ
ጠጥ ፡ ቍርባናቸውን ፡ እንደ ፡ ቍጥራቸው ፡
፳፰ መጠን ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፥ ለኃጢአትም ፡ መሥዋ
ዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፥ በዘወትር ፡ ከሚ
ቃጠለው ፡ መሥዋዕትና ፡ ከእህሉ ፡ ቍርባን ፡
ከመጠጡም ፡ ቍርባን ፡ ሌላ ፡ ታቀርባላችሁ ።

፳፱ በስድስተኛውም ፡ ቀን ፡ ስምንት ፡ ወይፈ
ኖች ፥ ሁለት ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ ነውር ፡ የሌለባ
ቸውን ፡ አሥራ ፡ አራት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡
፴ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፥ ለወይፈኖቹና ፡ ለአ
ውራ ፡ በጎቹ ፡ ለጠቦቶቹም ፡ የእህል ፡ ቍርባና
ቸውንና ፡ የመጠጥ ፡ ቍርባናቸውን ፡ እንደ ፡
፴፩ ቍጥራቸው ፡ መጠን ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፥ ለኃጢአ
ትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፥
በዘወትር ፡ ከሚቃጠለው ፡ መሥዋዕትና ፡ ከእ
ህሉ ፡ ቍርባን ፡ ከመጠጡም ፡ ቍርባን ፡ ሌላ ፡
ታቀርባላችሁ ።

፴፪ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ ሰባት ፡ ወይፈኖች ፥
ሁለት ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ ነውር ፡ የሌለባቸውን ፡
አሥራ ፡ አራት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ ተባት ፡ የበግ ፡
፴፫ ጠቦቶች ፥ ለወይፈኖቹና ፡ ለአውራ ፡ በጎቹ ፡
ለጠቦቶቹም ፡ የእህል ፡ ቍርባናቸውንና ፡ የመ
ጠጥ ፡ ቍርባናቸውን ፡ እንደ ፡ ቍጥራቸው ፡
፴፬ መጠን ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፥ ለኃጢአትም ፡ መሥዋ
ዕት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፥ በዘወትር ፡ ከሚ
ቃጠለው ፡ መሥዋዕትና ፡ ከእህሉ ፡ ቍርባን ፡
ከመጠጡም ፡ ቍርባን ፡ ሌላ ፡ ታቀርባላችሁ ።

፴፭ በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ የተቀደሰ ፡ ጉባኤ ፡
ይሁንላችሁ ፤ የተግባርን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አት
፴፮ ሥሩበት ። ለእግዚአብሔርም ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡
እንዲሆን ፡ በእሳት ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋ
ዕት ፥ አንድ ፡ ወይፈን ፥ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፥
ነውር ፡ የሌለባቸውን ፡ ሰባት ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡
፴፯ ተባት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ታቀርባላችሁ ። የእ
ህል ፡ ቍርባናቸውና ፡ የመጠጥ ፡ ቍርባናቸው ፡
ለወይፈኑ ፡ ለአውራውም ፡ በግ ፡ ለጠቦቶቹም ፡
እንደ ፡ ቍጥራቸው ፡ መጠን ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ ይሆ
፴፰ ናሉ ። ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ አንድ ፡
አውራ ፡ ፍየል ፡ ታቀርባላችሁ ፤ በዘወትር ፡ ከሚ
ቃጠለው ፡ መሥዋዕትና ፡ ከእህሉ ፡ ቍርባን ፡ ከመ
ጠጡም ፡ ቍርባን ፡ ሌላ ፡ የሚቀርቡ ፡ ናቸው ።
፴፱ እነዚህንም ፥ ከስእለታችሁና ፡ በፈቃዳችሁ ፡
ከምታመጡት ፡ ሌላ ፥ ለሚቃጠል ፡ መሥዋ
ዕት ፥ ለእህልም ፡ ለመጠጥም ፡ ቍርባን ፥ ለደኅ
ንነትም ፡ መሥዋዕታችሁ ፡ በበዓላችሁ ፡ ጊዜ ፡
፵ ለእግዚአብሔር ፡ አቅርቡ ። ሙሴም ፡ ለእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ ያዘዘ
ውን ፡ ሁሉ ፡ ነገራቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

፩ ሙሴም ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ነገዶች ፡ አለ
ቆች ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— እግዚ
፪ አብሔር ፡ ያዘዘው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ። ሰው ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ስእለት ፡ ቢሳል ፥ ወይም ፡
ራሱን ፡ በመሐላ ፡ ቢያስር ፥ ቃሉን ፡ አይስበር ፤
፫ ከአፉ ፡ እንደ ፡ ወጣው ፡ ሁሉ ፡ ያድርግ ። ሴትም ፡
ደግሞ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስእለት ፡ ብትሳል ፥
እርስዋም ፡ በአባትዋ ፡ ቤት ፡ ሳለች ፡ በብላቴን
ነትዋ ፡ ጊዜ ፡ ራስዋን ፡ በመሐላ ፡ ብታስር ፥
፬ አባትዋም ፡ ራስዋን ፡ ያሰረችበትን ፡ መሐላ ፡ ስእ
ለትዋንም ፡ ቢሰማ ፥ አባትዋም ፡ ዝም ፡ ቢላት ፥
ስእለትዋ ፡ ሁሉ ፡ ይጸናል ፥ ራስዋንም ፡ ያሰረ
፭ ችበት ፡ መሐላ ፡ ሁሉ ፡ ይጸናል ። አባትዋ ፡
ግን ፡ በሰማበት ፡ ቀን ፡ ቢከለክላት ፥ ስእለትዋ ፡
ራስዋንም ፡ ያሰረችበት ፡ መሐላዋ ፡ አይጸኑም ፤
አባትዋ ፡ ከልክሎአታልና ፡ እግዚአብሔር ፡
ይቅር ፡ ይላታል ።
፮ በተሳለችም ፡ ጊዜ ፡ ራስዋንም ፡ በመሐላ ፡
ያሰረችበት ፡ ነገር ፡ ከአፍዋ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ባል ፡
፯ ያገባች ፡ ብትሆን ፥ ባልዋም ፡ ቢሰማ ፥ በሰማ
በትም ፡ ቀን ፡ ዝም ፡ ቢላት ፥ ስእለትዋ ፡ ይጸ
ናል ፥ ራስዋንም ፡ ያሰረችበት ፡ መሐላ ፡ ይጸ
፰ ናል ። ባልዋ ፡ ግን ፡ በሰማበት ፡ ቀን ፡ ቢከለክ
ላት ፥ በእርስዋ ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ስእለትዋን ፡
ራስዋንም ፡ በመሐላ ፡ ያሰረችበትን ፡ የአፍዋን ፡
ነገር ፡ ከንቱ ፡ ያደርገዋል ፤ እግዚአብሔርም ፡
ይቅር ፡ ይላታል ።
፱ ባልዋ ፡ የሞተባት ፡ ወይም ፡ የተፋታች ፡ ግን ፡
ስእለትዋ ፡ ራስዋንም ፡ ያሰረችበት ፡ መሐላ ፡
፲ ይጸኑባታል ። ሴትም ፡ በባልዋ ፡ ቤት ፡ ሳለች ፡
ብትሳል ፥ ወይም ፡ ራስዋን ፡ በመሐላ ፡ ብታስር ፥
፲፩ ባልዋም ፡ ሰምቶ ፡ ዝም ፡ ቢላት ፡ ባይከለክላ
ትም ፥ ስእለትዋ ፡ ሁሉ ፡ ራስዋንም ፡ ያሰረች
፲፪ በት ፡ መሐላ ፡ ሁሉ ፡ ይጸናል ። ባልዋ ፡ ግን ፡
በሰማበት ፡ ቀን ፡ ከንቱ ፡ ቢያደርገው ፥ ስለ ፡ ስእ
ለትዋ ፡ ወይም ፡ ራስዋን ፡ ስላሰረችበት ፡ መሐላ ፡
ከአፍዋ ፡ የወጣው ፡ ነገር ፡ አይጸናም ፤ ባልዋ ፡
ከንቱ ፡ አድርጎታል ፤ እግዚአብሔርም ፡ ይቅር ፡
ይላታል ።
፲፫ ስእለትዋን ፡ ሁሉ ፡ ነፍስዋንም ፡ የሚያዋርደ
ውን ፡ መሐላ ፡ ሁሉ ፡ ባልዋ ፡ ያጸናዋል ፥ ባል
፲፬ ዋም ፡ ከንቱ ፡ ያደርገዋል ። ባልዋ ፡ ግን ፡ በየ
ዕለቱ ፡ ዝም ፡ ቢላት ፥ ስእለትዋን ፡ ሁሉ ፡ በእር
ስዋም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ መሐላ ፡ ሁሉ ፡ አጽን
ቶታል ፤ በሰማበት ፡ ቀን ፡ ዝም ፡ ብሎአታልና ፡
፲፭ አጽንቶታል ። ከሰማው ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ከንቱ ፡
፲፮ ቢያደርገው ፡ ኃጢአትዋን ፡ ይሸከማል ። እር
ስዋ ፡ በብላቴንነትዋ ፡ ጊዜ ፡ በአባትዋ ፡ ቤት ፡
ሳለች ፡ በአባትና ፡ በልጂቱ ፡ መከከል ፥ ወይም ፡
በባልና ፡ በሚስት ፡ መከከል ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡
እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ ያዘዘው ፡ ሥርዓት ፡
ይህ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፩ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪ ተናገረው ፡— ስለ ፡ እስራኤል ፡ ልጆች ፡ በቀል ፡
ምድያማውያንን ፡ ተበቀል ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡
፫ ወደ ፡ ወገኖችህ ፡ ትከማቻለህ ። ሙሴም ፡ ሕዝ
ቡን ፡— ከእናንተ ፡ መከከል ፡ ሰዎች ፡ ለጦርነት ፡
ይሰለፉ ፤ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ በቀል ፡ ምድያ
ምን ፡ ይበቀሉ ፡ ዘንድ ፡ በምድያም ፡ ላይ ፡
፬ ይሂዱ ፤ ከእስራኤል ፡ ነገዶች ፡ ሁሉ ፡ ከየነገዱ ፡
አንድ ፡ ሺህ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ጦርነት ፡ ስደዱ ፡
፭ ብሎ ፡ ተናገራቸው ። ከእስራኤልም ፡ አእላ
ፋት ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፥ ከየነገዱ ፡ አንድ ፡
አንድ ፡ ሺህ ፥ ለጦርነት ፡ የተሰለፉ ፡ ሰዎች ፡
፮ ተሰጡ ። ሙሴም ፡ ከየነገዱ ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡
ወደ ፡ ጦርነት ፡ ሰደደ ፤ እነርሱንና ፡ የካህኑን ፡
የአልዓዛርን ፡ ልጅ ፡ ፊንሐስን ፡ ወደ ፡ ጦርነት ፡
ሰደዳቸው ፤ የመቅደሱንም ፡ ዕቃ ፡ የሚነፋው
፯ ንም ፡ መለከት ፡ በእጁ ፡ ሰጠው ። እግዚአብ
ሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘ ፡ ከምድያም ፡ ጋር ፡
፰ ተዋጉ ፥ ወንዶችንም ፡ ሁሉ ፡ ገደሉ ። ከተገ
ደሉትም ፡ ጋር ፡ የምድያምን ፡ ነገሥታት ፡ ገደ
ሉአቸው ፤ አምስቱም ፡ የምድያም ፡ ነገሥታት ፡
ኤዊ ፥ ሮቆም ፥ ሱር ፥ ሑር ፥ ሬባ ፡ ነበሩ ፤ የቢ
ዖርንም ፡ ልጅ ፡ በለዓምን ፡ ደግሞ ፡ በሰይፍ ፡
፱ ገደሉት ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ የምድያ
ምን ፤ ሴቶችና ፡ ልጆቻቸውን ፡ ማረኩ ፤ እንስ
ሶቻቸውንና ፡ መንጎቻቸውንም ፡ ዕቃቸውንም ፡
፲ ሁሉ ፡ በዘበዙ ። የተቀመጡባቸውን ፡ ከተሞ
ቻቸውን ፡ ሁሉ ፡ ሰፈሮቻቸውንም ፡ ሁሉ ፡ በእ
፲፩ ሳት ፡ አቃጠሉ ። የሰውንና ፡ የእንስሳን ፡ ምር
፲፪ ኮና ፡ ብዝበዛ ፡ ሁሉ ፡ ወሰዱ ። የማረኩአቸው
ንም ፡ ሰዎች ፡ ምርኮውንና ፡ ብዝበዛውን ፡ ወደ ፡

ሙሴና ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ወደ ፡ አልዓዛር ፡ ወደ ፡
እስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ÷ በዮርዳኖስም ፡
አጠገብ ፡ በኢያሪኮ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በሞዓብ ፡
ሜዳ ፡ ወዳለው ፡ ሰፈር ፡ አመጡ ።

፲፫ ሙሴና ፡ ካህኑ ፡ አልዓዛርም ፡ የማኅበሩም ፡
አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ከሰፈሩ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ሊገና
፲፬ ኙአቸው ፡ ወጡ ። ሙሴም ፡ ከዘመቻ ፡ በተመለ
ሱት ፡ በጭፍራ ፡ አለቆች ÷ በሻለቆችና ፡ በመቶ ፡
፲፭ አለቆች ፡ ላይ ፡ ተቈጣ ። ሙሴም ፡ አላቸው ፡—
በውኑ ፡ ሴቶችን ፡ ሁሉ ፡ አዳናችኋቸውን ?
፲፮ እነሆ ÷ እነዚህ ፡ በፌጎር ፡ ምክንያት ፡ በበለዓም ፡
ምክር ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይበድሉ ፡ ዘንድ ፡
ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ዕንቅፋት ፡ ሆኑ ፤ ስለዚ
ህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ማኅበር ፡ ላይ ፡ መቅሠ
፲፯ ፍት ፡ ሆነ ። አሁን ፡ እንግዲህ ፡ ከልጆቹ ፡ ወን
ዱን ፡ ሁሉ ፡ ግደሉ ÷ ወንድንም ፡ በመኝታ ፡
፲፰ የሚያውቁትን ፡ ሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ግደሉ ። ወንድን ፡
የማያውቁትን ፡ ሴቶች ፡ ልጆችን ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡
፲፱ ለራሳችሁ ፡ አድኑአቸው ። ከሰፈሩም ፡ ውጭ ፡
ሰባት ፡ ቀን ፡ ስፈሩ ፤ ሰውን ፡ የገደለ ፡ ሁሉ ፡
የተገደለውንም ፡ የዳሰሰ ፡ ሁሉ ÷ እናንተ ፡ የማ
ረካችኋቸውም ፡ በሦስተኛውና ፡ በሰባተኛው ፡
፳ ቀን ፡ ሰውነታችሁን ፡ ንጹሕ ፡ አድርጉ ። ልብ
ስንም ÷ ከቍርበትም ፡ የተዘጋጀውን ፡ ሁሉ ÷
ከፍየልም ፡ ጠጕር ፡ ከእንጨትም ፡ የተሠራ
ውን ፡ ሁሉ ፡ ንጹሕ ፡ አድርጉ ።

፳፩ ካህኑም ፡ አልዓዛር ፡ ከሰልፍ ፡ የመጡትን ፡
ሰዎች ፡ አላቸው ፡— እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡
፳፪ ያዘዘው ፡ የሕጉ ፡ ሥርዓት ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ወርቁ
ንና ፡ ብሩን ÷ ናሱንም ÷ ብረቱንም ÷ ቆርቆሮው
፳፫ ንም ÷ አረሩንም ÷ በእሳት ፡ ለማለፍ ፡ የሚችለ
ውን ፡ ሁሉ ፡ በእሳት ፡ ታሳልፉታላችሁ ÷ ንጹ
ሕም ፡ ይሆናል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በማንጻት ፡ ውኃ ፡
ደግሞ ፡ ይጠራል ። በእሳትም ፡ ለማለፍ ፡ የማ
፳፬ ይችለውን ፡ በውኃ ፡ ታሳልፉታላችሁ ። በሰባ
ተኛውም ፡ ቀን ፡ ልብሳችሁን ፡ እጠቡ ÷ ንጹ
ሕም ፡ ትሆናላችሁ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡
ሰፈሩ ፡ ትቀርባላችሁ ።

፳፭ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፳፮ ተናገረው ፡— አንተና ፡ ካህኑ ፡ አልዓዛር ፡ የማ
ኅበሩም ፡ አባቶች ፡ አለቆች ፡ የተማረኩትን ፡
፳፯ ሰውና ፡ እንስሳ ፡ ቍጠሩ ። ምርኮውንም ፡ በተ
ዋጉትና ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ በወጡት ÷ በማኅበ
ሩም ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ አስተካክለህ ፡ ክፈል ።
፳፰ ከእነዚያም ፡ ከተዋጉት ፡ ወደ ፡ ሰልፍም ፡ ከወ
ጡት ፡ ሰልፈኞች ፡ ዘንድ ÷ ከሰዎችም ፡ ከበሬ
ዎችም ፡ ከአህዮችም ፡ ከመንጎችም ፡ ከአም
ስት ፡ መቶ ፡ አንድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ግብር ፡
፳፱ አውጣ ። ከድርሻቸው ፡ ወስደህ ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ ለማንሣት ፡ ቍርባን ፡ ለካህኑ ፡ ለአልዓ
፴ ዛር ፡ ስጠው ። ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ድርሻ ፡
ከሰዎች ፡ ከበሬዎችም ፡ ከአህዮችም ፡ ከመንጎ
ችም ፡ ከከብቶችም ፡ ሁሉ ፡ ከአምሳ ፡ አንድ ፡
ትወስዳለህ ÷ የእግዚአብሔርንም ፡ ማደሪያ ፡
አገልግሎት ፡ ለሚጠብቁ ፡ ለሌዋውያን ፡ ትሰጣ
፴፩ ለህ ። ሙሴና ፡ ካህኑ ፡ አልዓዛርም ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ አደረጉ ።

፴፪ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የወጡ ፡ ሰዎችም ፡ ከወሰዱት ፡
ብዝበዛ ፡ ያስቀሩት ፡ ምርኮ ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤
ስድስት ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ በጎች ÷
፴፫ ፴፬ ሰባ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ በሬዎች ÷ ስድሳ ፡ አንድ ፡
፴፭ ሺህ ፡ አህዮች ÷ ወንድ ፡ ከማያውቁ ፡ ሴቶችም ፡
፴፮ ሠላሳ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ነፍስ ። በዘመቻም ፡ ለነበሩ ፡
ሰዎች ፡ ድርሻ ፡ የሆነ ፡ እኩሌታ ፡ ከበግ ፡ ሦስት ፡
መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡
፴፯ በጎች ፡ ነበረ ÷ ከበጎችም ፡ የእግዚአብሔር ፡
፴፰ ግብር ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡ አምስት ፡ ነበረ ። በሬ
ዎችም ፡ ሠላሳ ፡ ስድስት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡
ነበሩ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ግብር ፡ ሰባ ፡ ሁለት ፡
፴፱ ነበረ ። አህዮቹም ፡ ሠላሳ ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡
መቶ ፡ ነበሩ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ግብር ፡ ስድሳ ፡
፵ አንድ ፡ ነበረ ። ሰዎቹም ፡ አሥራ ፡ ስድስት ፡
ሺህ ፡ ነበሩ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ግብር ፡ ሠላሳ ፡
፵፩ ሁለት ፡ ነበረ ። እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እን
ዳዘዘው ፡ ሙሴ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለማንሣት ፡
ቍርባን ፡ የሆነውን ፡ ግብር ፡ ለካህኑ ፡ ለአል
ዓዛር ፡ ሰጠው ።

፵፪ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እኩሌታም ÷ ወደ ፡
ሰልፍ ፡ ከወጡት ፡ ወንዶች ፡ ላይ ፡ ሙሴ ፡ የለ
፵፫ የው ÷ የማኅበሩ ፡ ድርሻ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡
፵፬ ሰባት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ በጎች ÷ ሠላሳ ፡
፵፭ ስድስት ፡ ሺህ ፡ በሬዎች ÷ ሠላሳ ፡ ሺህ ፡ አም
፵፮ ስት ፡ መቶ ፡ አህዮች ÷ አሥራ ፡ ስድስት ፡ ሺህ ፡
፵፯ ሰዎች ፡ ነበሩ ። ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ድርሻ ፡
ሙሴ ፡ ከሰውና ፡ ከእንስሳ ፡ ከአምሳ ፡ አንድ ፡
ወሰደ ÷ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ማደሪያ ፡ አገልግሎት ፡ ለሚ
ጠብቁ ፡ ሌዋውያን ፡ ሰጠ ።

፵፰ በሠራዊት ፡ እእላፋት ፡ ላይ ፡ የተሾሙት ፡
አለቆች ÷ ሻለቆችና ፡ የመቶ ፡ አለቆች ÷ ወደ ፡
፵፱ ሙሴ ፡ ቀረቡ ÷ ሙሴንም ፡— እኛ ፡ ባሪያዎችህ ፡
ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የወጡትን ፡ ከእጃችን ፡ በታች ፡
ያሉትን ፡ ቈጠርን ÷ ከእኛም ፡ አንድ ፡ አልጐ
፶ ደለም ። ሰውም ፡ ሁሉ ፡ ካገኘው ፡ ከወርቅ ፡
ዕቃ ÷ ከእግር ፡ አልቦም ÷ ከአምባርም ÷ ከቀለ
በትም ÷ ከጕትቻም ÷ ከድሪውም ፡ ለነፍሳችን ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያስተሰርይልን ፡ ዘንድ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ መባ ፡ አምጥተናል ፡ አሉት ።
፶፩ ሙሴና ፡ ካህኑ ፡ አልዓዛርም ፡ ወርቁንና ፡ በልዩ ፡
ልዩ ፡ የተሠራውን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ከእጃቸው ፡
፶፪ ተቀበሉ ። ሻለቆችም ፡ የመቶ ፡ አለቆችም ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ለማንሣት ፡ ቍርባን ፡ ያቀረ
ቡት ፡ ወርቅ ፡ ሁሉ ፡ አሥራ ፡ ስድስት ፡ ሺህ ፡
፶፫ ሰባት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ሰቅል ፡ ነበረ ። ወደ ፡
ሰልፍ ፡ የወጡ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ከምርኮአቸው ፡
፶፬ ለራሳቸው ፡ ወሰዱ ። ሙሴና ፡ ካህኑ ፡ አልዓዛ
ርም ፡ ወርቁን ፡ ከሻለቆችና ፡ ከመቶ ፡ አለቆች ፡
ወስደው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለእስራኤል ፡

ልጆች ፡ መታሰቢያ ፡ ወደ ፡ መገናኛው ፡ ድን
ኳን ፡ አገቡት ።

ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

፩፡ የሮቤልና ፡ የጋድ ፡ ልጆችም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡
እንስሶች ፡ ነበሩአቸው ፤ እነሆም ፥ የኢያዜር ፡
ምድርና ፡ የገለዓድ ፡ ምድር ፡ ለእንስሶች ፡ የተ
፪፡ መቸ ፡ ስፍራ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፥ የጋ
ድና ፡ የሮቤል ፡ ልጆች ፡ መጥተው ፡ ሙሴንና ፡
ካህኑን ፡ አልዓዛርን ፡ የማኅበሩንም ፡ አለቆች ፡
፫፡፬፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ ተናገሩአቸው ፦ እግዚአብ
ሔር ፡ በእስራኤል ፡ ማኅበር ፡ ፊት ፡ የመታው ፡
ምድር ፥ አጣሮት ፥ ዲቦን ፥ ኢያዜር ፥ ነምራ ፥
ሐሴቦን ፥ ኤልያሊ ፥ ሴባማ ፥ ናባው ፥ ባያን ፥
ለእንስሶች ፡ የተመቸ ፡ ምድር ፡ ነው ፤ ለእኛም ፡
፭፡ ለባሪያዎችህ ፡ እንስሶች ፡ አሉን ። እኛስ ፡ በአ
ንተ ፡ ዘንድ ፡ ሞገስን ፡ አግኝተን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ይህን ፡ ምድር ፡ ለባሪያዎችህ ፡ ርስት ፡ አድር
ገህ ፡ ስጠን ፤ ወደ ፡ ዮርዳኖስም ፡ ማዶ ፡ አታሻግ
ረን ።

፮፡ ሙሴም ፡ ለጋድና ፡ ለሮቤል ፡ ልጆች ፡ አላ
ቸው ፦ ወንድሞቻችሁ ፡ ወደ ፡ ጦርነት ፡ ሲሄዱ ፡
፯፡ እናንተ ፡ በዚህ ፡ ትቀመጣላችሁን ? እግዚአብ
ሔር ፡ ወደሚሰጣቸው ፡ ምድር ፡ እንዳይሻገሩ ፡
የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ልብ ፡ ለምን ፡ ታደክማ
፰፡ ላችሁ ? ምድሪቱን ፡ ይሰልሉ ፡ ዘንድ ፡ ከቃዴስ ፡
በርኔ ፡ በሰደድኋቸው ፡ ጊዜ ፡ አባቶቻችሁ ፡ እን
፱፡ ዲህ ፡ አደረጉ ። ወደ ፡ ኤሽኮልም ፡ ሸለቆ ፡
በሄዱ ፡ ጊዜ ፥ ምድሪቱንም ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፥ እግ
ዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ሰጣቸው ፡ ምድር ፡ እንዳይ
ገቡ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ልብ ፡ አደከሙ ።
፲፡ በዚያም ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ ነደደ ፥
፲፩፡፲፪፡ እርሱም ፦ በእውነት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈጽ
መው ፡ ከተከተሉ ፡ ከእነዚህ ፡ ከቄኔዛዊው ፡ ከዮ
ፎኒ ፡ ልጅ ፡ ከካሌብና ፡ ከነዌ ፡ ልጅ ፡ ከኢያሱ ፡
በቀር ፥ ከግብፅ ፡ የወጡት ፡ ከሀያ ፡ ዓመት ፡
ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፡ ሰዎች ፡ እኔን ፡
ፈጽመው ፡ አልተከተሉምና ፡ ለአብርሃምና ፡
ለይስሐቅ ፡ ለያዕቆብም ፡ እሰጥ ፡ ዘንድ ፡ የማል
፲፫፡ ሁበትን ፡ ምድር ፡ አያዩም ፡ ብሎ ፡ ማለ ። የእግ
ዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ጸና ፥
በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ያደረገ ፡ ትው
ልድ ፡ ሁሉ ፡ እስኪጠፉ ፡ ድረስ ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡
፲፬፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ውስጥ ፡ አቅበዘበዛቸው ። እነ
ሆም ፥ የእግዚአብሔርን ፡ መዓት ፡ በእስራኤል ፡
ላይ ፡ አብዝታችሁ ፡ ትጨምሩ ፡ ዘንድ ፡ እናንተ ፡
የኃጢአተኞች ፡ ትውልድ ፡ በአባቶቻችሁ ፡
፲፭፡ ፋንታ ፡ ቆማችኋል ። እርሱን ፡ ከመከተል ፡ ብት
መለሱ ፡ እርሱ ፡ ሕዝቡን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ደግሞ ፡
ይተዋል ፤ ይህንንም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ታጠፉላ
ችሁ ።

፲፮፡ ወደ ፡ እርሱም ፡ ቀርበው ፡ አሉት ፦ በዚህ ፡
ለእንስሶቻችን ፡ በረቶች ፡ ለልጆቻችንም ፡ ከተ
፲፯፡ ሞች ፡ እንሠራለን ፤ እኛ ፡ ግን ፡ ለጦርነት ፡ ተዘ
ጋጅተን ፡ ወደ ፡ ስፍራቸው ፡ እስክናገባቸው ፡
ድረስ ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ እንሄዳለን ፤
በዚህም ፡ ምድር ፡ ስላሉ ፡ ሰዎች ፡ ልጆቻችን ፡
፲፰፡ በተመሸጉ ፡ ከተሞች ፡ ይቀመጣሉ ። የእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ርስታቸውን ፡ እስኪወርሱ ፡
፲፱፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ቤቶቻችን ፡ አንመለስም ፤ ከዮር
ዳኖስ ፡ ወዲህ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ርስታችን ፡
ደርሶናልና ፡ እኛ ፡ ከዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ወደዚያ ፡
ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ርስት ፡ አንወርስም ።

፳፡ ሙሴም ፡ አላቸው ፦ ይህንስ ፡ ነገር ፡ ብታደ
ርጉ ፥ ተዘጋጅታችሁም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
፳፩፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ ብትሄዱ ፥ እርሱም ፡ ጠላቶቹን ፡
ከፊቱ ፡ እስኪያሰድድ ፡ ድረስ ፡ ምድሪቱም ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ድል ፡ እስክትሆን ፡
ድረስ ፡ ከእናንተ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ጋሻ ፡ ጦሩን ፡
ይዞ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ዮርዳኖስን ፡ ቢሻ
፳፪፡ ገር ፥ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ትመለሳላችሁ ፥ በእግዚ
አብሔርም ፡ ፊት ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ንጹ
ሐን ፡ ትሆናላችሁ ፤ ይህች ፡ ምድርም ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ርስት ፡ ትሆንላችኋለች ።
፳፫፡ እናንተ ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ ባታደርጉ ፥ እነሆ ፥
እግዚአብሔርን ፡ ትበድላላችሁ ፤ ኃጢአታች
፳፬፡ ሁም ፡ እንዲያገኛችሁ ፡ እወቁ ። ለልጆቻችሁ ፡
ከተሞች ፥ ለበጎቻችሁም ፡ በረቶች ፡ ሥሩ ፤
ከአፋችሁም ፡ የወጣውን ፡ ነገር ፡ አድርጉ ።

፳፭፡ የጋድና ፡ የሮቤልም ፡ ልጆች ፡ ሙሴን ፡ እን
ዲህ ፡ ብለው ፡ ተናገሩት ፦ እኛ ፡ ባሪያዎችህ ፡
፳፮፡ ጌታችን ፡ እንዳዘዘ ፡ እናደርጋለን ። ልጆቻችን ፥
ሚስቶቻችንም ፥ መንጎቻችንም ፥ እንስሶቻች
ንም ፡ ሁሉ ፡ በዚያ ፡ በገለዓድ ፡ ከተሞች ፡ ይሆ
፳፯፡ ናሉ ፤ እኛ ፡ ባሪያዎችህ ፡ ግን ፡ ሁላችን ፡ ጋሻ ፡
ጦራችንን ፡ ይዘን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ጌታችን ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ወደ ፡ ጦርነት ፡ እንሄ
ዳለን ።

፳፰፡ ሙሴም ፡ ካህኑን ፡ አልዓዛርን ፡ የነዌንም ፡
ልጅ ፡ ኢያሱን ፡ የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡
፳፱፡ አለቆች ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ አዘዘ ። ሙሴም ፦
የጋድና ፡ የሮቤል ፡ ልጆች ፡ ሁላቸው ፡ ጋሻ ፡
ጦራቸውን ፡ ይዘው ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ ፊት ፡ ዮርዳኖስን ፡ ቢሻገሩ ፥ ምድሪ
ቱንም ፡ ድል ፡ ብትነሡ ፥ የገለዓድን ፡ ምድር ፡
፴፡ ርስት ፡ አድርጋችሁ ፡ ትሰጡአቸዋላችሁ ። ጋሻ ፡
ጦራቸውን ፡ ይዘው ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ባይሻ
ገሩ ፡ ግን ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ በእናንተ ፡ መካ
፴፩፡ ከል ፡ ርስታቸውን ፡ ይወርሳሉ ፡ አላቸው ። የጋ
ድና ፡ የሮቤልም ፡ ልጆች ፡ መልሰው ፦ እግዚ
አብሔር ፡ ለእኛ ፡ ለባሪያዎችህ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡
፴፪፡ እንዲሁ ፡ እናደርጋለን ። ጋሻ ፡ ጦራችንን ፡
ይዘን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ከነዓን ፡
ምድር ፡ እንሻገራለን ፥ ከዮርዳኖስም ፡ ማዶ ፡
ከወዲሁ ፡ የወረስነው ፡ ርስት ፡ ይሆንልናል ፡
አሉት ።

፴፫፡ ሙሴም ፡ ለጋድና ፡ ለሮቤል ፡ ልጆች ፡ ለዮሴ
ፍም ፡ ልጅ ፡ ለምናሴ ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፥ የአ

ሞራውያንን ፡ ንጉሥ ፡ የሴዎንን ፡ ግዛት ፡ የባሳ
ንንም ፡ ንጉሥ ፡ የዐግን ፡ ግዛት ÷ ምድሪቱንና ፡
በዙሪያዋ ፡ ያሉትን ፡ ከተሞች ፡ ሰጣቸው ።
፴፬ የጋድም ፡ ልጆች ፡ ዲቦንን ÷ አጣሮትን ÷ አሮዔ
፴፭ ርን ÷ ዓጥሮትሽፋንን ÷ ኢያዜርን ÷ ዮግብሃን ÷
፴፮ ቤትነምራን ÷ ቤትሃራንን ፡ የተመሸጉ ፡ ከተ
ሞች ፡ አድርገው ፡ ሠሩ ፤ የበጎች ፡ በረቶችንም ፡
፴፯ ሠሩ ። የሮቤልም ፡ ልጆች ፡ ሐሴቦንን ÷ ኤልያ
፴፰ ሌን ÷ ቂርያታይምን ÷ ስማቸውም ፡ የተለወጠ
ውን ፡ ናባውን ÷ በአልሜዎንን ÷ ሴባማን ፡
ሠሩ ፤ እነዚህንም ፡ የሠሩአቸውን ፡ ከተሞች ፡
፴፱ በሌላ ፡ ስም ፡ ጠሩአቸው ። የምናሴም ፡ ልጅ ፡
የማኪር ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ገለዓድ ፡ ሄዱ ÷ ወሰ
ዱአትም ÷ በእርስዋም ፡ የነበሩትን ፡ አሞራው
፵ ያንን ፡ አሳደዱ ። ሙሴም ፡ ለምናሴ ፡ ልጅ ፡
ለማኪር ፡ ገለዓድን ፡ ሰጠ ፤ በእርስዋም ፡ ተቀ
፵፩ መጠ ። የምናሴም ፡ ልጅ ፡ ኢያዕር ፡ ሄዶ ፡ መን
ደሮችዋን ፡ ወሰደ ÷ የኢያዕርም ፡ መንደሮች ፡
፵፪ ብሎ ፡ ጠራቸው ። ኖባህም ፡ ሄደ ፡ ቄናትንም ፡
መንደሮችዋንም ፡ ወሰደ ÷ በስሙም ፡ ኖባህ ፡
ብሎ ፡ ጠራቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፫ ።

፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ጕዞ ፡ ከሙሴና ፡ ከአ
ሮን ፡ እጅ ፡ በታች ፡ በጭፍሮቻቸው ፡ ከግብፅ ፡
፪ በወጡ ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ ነበረ ። ሙሴም ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ እንደ ፡ ጕዞአቸው ፡ አወ
ጣጣቸውን ፡ ጻፈ ፤ እንደ ፡ አወጣጣቸውም ፡
፫ ጕዞአቸው ፡ እንዲህ ፡ ነበረ ። በመጀመሪያው ፡
ወር ፡ ከወሩም ፡ በአሥራ ፡ አምስተኛው ፡ ቀን ፡
ከራምሴ ፡ ተጓዙ ፤ ከፋሲካ ፡ በኋላ ፡ በነጋው ፡
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ግብፃውያን ፡ ሁሉ ፡ እያዩ ፡
፬ ከፍ ፡ ባለች ፡ እጅ ፡ ወጡ ። በዚያም ፡ ጊዜ ፡
ግብፃውያን ፡ እግዚአብሔር ፡ የገደላቸውን ፡
በኵሮቻቸውን ፡ ይቀብሩ ፡ ነበር ፤ በአማልክቶ
ቻቸውም ፡ ደግሞ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈረደባ
ቸው ።

፭ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከራምሴ ፡ ተጕዘው ፡
፮ በሱኮት ፡ ሰፈሩ ። ከሱኮትም ፡ ተጕዘው ፡ በም
ድረ ፡ በዳ ፡ ዳርቻ ፡ ባለች ፡ በኤታም ፡ ሰፈሩ ።
፯ ከኤታምም ፡ ተጕዘው ፡ በበአልዛፎን ፡ ፊት ፡
ወደ ፡ ነበረች ፡ ወደ ፡ ፊሀሒሮት ፡ ተመለሱ ፤
፰ በሚግዶልም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ሰፈሩ ። ከፊሀሒ
ሮትም ፡ ተጕዘው ፡ በባሕሩ ፡ ውስጥ ፡ ወደ ፡
ምድረ ፡ በዳ ፡ አለፉ ፤ በኤታምም ፡ በረሀ ፡ የሦ
ስት ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ ሄደው ፡ በማራ ፡ ሰፈሩ ።
፱ ከማራም ፡ ተጕዘው ፡ ወደ ፡ ኤሊም ፡ መጡ ፤
በኤሊምም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ የውኃ ፡ ምንጮች ፡
ሰባ ፡ ዘንባባዎችም ፡ ነበሩ ፤ በዚያም ፡ ሰፈሩ ።
፲ ከኤሊምም ፡ ተጕዘው ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡
፲፩ ዳር ፡ ሰፈሩ ። ከኤርትራም ፡ ባሕር ፡ ተጕዘው ፡
፲፪ በሲን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሰፈሩ ። ከሲን ፡ ምድረ ፡
፲፫ በዳም ፡ ተጕዘው ፡ በራፋቃ ፡ ሰፈሩ ። ከራፋ
፲፬ ቃም ፡ ተጕዘው ፡ በኤሉስ ፡ ሰፈሩ ። ከኤሉስም ፡
ተጕዘው ፡ በራፊዲም ፡ ሰፈሩ ፡ በዚያም ፡ ሕዝቡ ፡
፲፭ የሚጠጡት ፡ ውኃ ፡ አልነበረም ። ከራፊዲምም ፡
፲፮ ተጕዘው ፡ በሲና ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሰፈሩ ። ከሲ
ናም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ተጕዘው ፡ በምኞት ፡ መቃ
፲፯ ብር ፡ ሰፈሩ ። ከምኞት ፡ መቃብርም ፡ ተጕዘው ፡
፲፰ በሐጼሮት ፡ ሰፈሩ ። ከሐጼሮትም ፡ ተጕዘው ፡
፲፱ በሪትማ ፡ ሰፈሩ ። ከሪትማም ፡ ተጕዘው ፡ በሬ
፳ ሞን ፡ ዘፋሬስ ፡ ሰፈሩ ። ከሬሞን ፡ ዘፋሬስም ፡
፳፩ ተጕዘው ፡ በልብና ፡ ሰፈሩ ። ከልብናም ፡ ተጕ
፳፪ ዘው ፡ በሪሳ ፡ ሰፈሩ ። ከሪሳም ፡ ተጕዘው ፡ በቀ
፳፫ ሄላታ ፡ ሰፈሩ ። ከቀሄላታም ፡ ተጕዘው ፡ በሻ
፳፬ ፍር ፡ ተራራ ፡ ሰፈሩ ። ከሻፍር ፡ ተራራም ፡ ተጕ
፳፭ ዘው ፡ በሐራዳ ፡ ሰፈሩ ። ከሐራዳም ፡ ተጕዘው ፡
፳፮ በመቅሄሎት ፡ ሰፈሩ ። ከመቅሄሎትም ፡ ተጕ
፳፯ ዘው ፡ በታሐት ፡ ሰፈሩ ። ከታሐትም ፡ ተጕዘው ፡
፳፰ በታራ ፡ ሰፈሩ ። ከታራም ፡ ተጕዘው ፡ በሚ
፳፱ ትቃ ፡ ሰፈሩ ። ከሚትቃም ፡ ተጕዘው ፡ በሐሽ
፴ ሞና ፡ ሰፈሩ ። ከሐሽሞናም ፡ ተጕዘው ፡ በሞሴ
፴፩ ሮት ፡ ሰፈሩ ። ከሞሴሮትም ፡ ተጕዘው ፡ በብኔ
፴፪ ያዕቃን ፡ ሰፈሩ ። ከብኔያዕቃንም ፡ ተጕዘው ፡
፴፫ በሖርሃጊድጋድ ፡ ሰፈሩ ። ከሖርሃጊድጋድም ፡
፴፬ ተጕዘው ፡ በዮጥባታ ፡ ሰፈሩ ። ከዮጥባታም ፡
፴፭ ተጕዘው ፡ በዔብሮና ፡ ሰፈሩ ። ከዔብሮናም ፡
፴፮ ተጕዘው ፡ በዔጽዮንጋብር ፡ ሰፈሩ ። ከዔጽዮ
ንጋብርም ፡ ተጕዘው ፡ በጺን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
፴፯ ሰፈሩ ፤ ይህችም ፡ ቃዴስ ፡ ናት ። ከቃዴስም ፡
ተጕዘው ፡ በኤዶምያስ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ባለው ፡
በሖር ፡ ተራራ ፡ ሰፈሩ ።

፴፰ ካህኑም ፡ አሮን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡
ወደ ፡ ሖር ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ወጣ ÷ በዚያም ፡ የእ
ስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ከወጡ ፡
በኋላ ፡ በአርባኛው ፡ ዓመት ፡ በአምስተኛው ፡
ወር ፡ ከወሩም ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ሞተ ።
፴፱ አሮንም ፡ በሖር ፡ ተራራ ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ ዕድ
ሜው ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ነበረ ።

፵ በከነዓን ፡ ምድርም ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ተቀ
ምጦ ፡ የነበረው ፡ ከነዓናዊው ፡ የዓራድ ፡ ንጉሥ ፡
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ መጡ ፡ ሰማ ።

፵፩ እነርሱም ፡ ከሖር ፡ ተራራ ፡ ተጕዘው ፡ በሴል
፵፪ ሞና ፡ ሰፈሩ ። ከሴልሞናም ፡ ተጕዘው ፡ በፉ
፵፫ ኖን ፡ ሰፈሩ ። ከፉኖንም ፡ ተጕዘው ፡ በአቦት ፡
፵፬ ሰፈሩ ። ከአቦትም ፡ ተጕዘው ፡ በሞዓብ ፡ ዳርቻ ፡
፵፭ ባለው ፡ በጋይ ፡ ሰፈሩ ። ከጋይም ፡ ተጕዘው ፡
፵፮ በዲቦንጋድ ፡ ሰፈሩ ። ከዲቦንጋድም ፡ ተጕዘው ፡
፵፯ በዓልሞንዲብላታይም ፡ ሰፈሩ ። ከዓልሞንዲ
ብላታይምም ፡ ተጕዘው ፡ በናባው ፡ ፊት ፡
ባሉት ፡ በዓባሪም ፡ ተራሮች ፡ ላይ ፡ ሰፈሩ ።
፵፰ ከዓባሪምም ፡ ተራሮች ፡ ተጕዘው ፡ በዮርዳኖስ ፡
አጠገብ ፡ በኢያሪኮ ፡ ፊት ፡ ባለው ፡ በሞዓብ ፡
፵፱ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ሰፈሩ ። በዮርዳኖስም ፡ አጠገብ ፡
በሞዓብ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ከቤትየሺሞት ፡ እስከ ፡
አቤልሰጢም ፡ ድረስ ፡ ሰፈሩ ።

፶ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ በዮርዳኖስ ፡ አጠ
ገብ ፡ በኢያሪኮ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በሞዓብ ፡ ሜዳ ፡

፶፩ ላይ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— ወደ ፡ ከነዓን ፡ ምድር ፡ ዮርዳኖስን ፡ በተሻገራችሁ ፡ ፶፪ ጊዜ ÷ የአገሩን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ከፊታችሁ ፡ ታሳድዳላችሁ ÷ የተቀረጹትንም ፡ ድንጋዮቻቸ ውን ፡ ሁሉ ፡ ታጠፋላችሁ ÷ ቀልጠው ፡ የተሠ ሩትንም ፡ ምስሎቻቸውን ፡ ሁሉ ፡ ታጠፋላችሁ ÷ በኮረብታ ፡ ላይ ፡ ያሉትን ፡ መስገጃዎቻቸውንም ፡ ፶፫ ታፈርሳላችሁ ፤ ምድሪቱንም ፡ ለእናንተ ፡ ርስት ፡ አድርጌ ፡ ሰጥቼአችኋለሁና ፡ ምድሪቱን ፡ ትወር ፶፬ ሱአታላችሁ ፡ ትቀመጡባታላችሁም ። ምድ ሪቱንም ፡ በየወገኖቻችሁ ፡ በዕጣ ፡ ትወርሳላ ችሁ ፤ ለብዙዎች ፡ እንደ ፡ ብዛታቸው ፡ ለጥቂ ቶቹም ፡ እንደ ፡ ጥቂትነታቸው ፡ መጠን ፡ ርስ ትን ፡ ትሰጣላችሁ ፤ እያንዳንዱ ፡ ሁሉ ፡ ዕጣ ፡ እንደ ፡ ወደቀለት ፡ በዚያ ፡ ርስቱ ፡ ይሆናል ፤ ፶፭ በየአባቶቻችሁ ፡ ነገዶች ፡ ትወርሳላችሁ ። የአ ገሩንም ፡ ሰዎች ፡ ከፊታችሁ ፡ ባታሳድዱ ÷ ያስ ቀራችኋቸው ፡ ለዓይናችሁ ፡ እንደ ፡ እሾህ ፡ ለጎ ናችሁም ፡ እንደሚወጋ ፡ ነገር ፡ ይሆኑባችኋል ÷ በምትቀመጡባትም ፡ ምድር ፡ ያስጨንቁአች ፶፮ ኋል ። እኔም ፡ በእነርሱ ፡ አደርገው ፡ ዘንድ ፡ ያሰብሁትን ፡ በእናንተ ፡ አደርግባችኋለሁ ።

## ምዕራፍ ፴፬ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፪ ተናገረው ፡— የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ እዘዛቸው ፡— ወደ ፡ ከነዓን ፡ ምድር ፡ በገባችሁ ፡ ጊዜ ÷ ርስት ፡ ትሆናችሁ ፡ ዘንድ ፡ በዕጣ ፡ የምትደርሳችሁ ፡ ምድር ÷ በዳርቻዋ ፡ ፫ ያለች ፡ የከነዓን ፡ ምድር ÷ ይህች ፡ ናት ፤ የደቡቡ ፡ ወገን ፡ ከጺን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በኤዶምያስ ፡ በኩል ፡ ይሆናል ፤ የደቡቡም ፡ ዳርቻ ፡ ከጨው ፡ ባሕር ፡ ፬ ዳር ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ይጀምራል ፤ ዳር ቻችሁም ፡ በአቅረቢም ፡ ዐቀበት ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ይዞራል ፡ ወደ ፡ ጺንም ፡ ያልፋል ፤ መውጫውም ፡ በቃዴስ ፡ በርኔ ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ይሆናል ፤ ወደ ፡ ሐጸርአዳር ፡ ይሄዳል ፡ ፭ ወደ ፡ ዓጽሞንም ፡ ያልፋል ፤ ዳርቻውም ፡ ከዓ ጽሞን ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ወንዝ ፡ ይዞራል ÷ መው ጫውም ፡ በባሕሩ ፡ በኩል ፡ ይሆናል ።

፮ ለምዕራብም ፡ ዳርቻ ፡ ታላቁ ፡ ባሕር ፡ ዳርቻ ችሁ ፡ ይሆናል ፤ ይህ ፡ የምዕራብ ፡ ዳርቻችሁ ፡ ይሆናል ።

፯ የሰሜንም ፡ ዳርቻችሁ ፡ ይህ ፡ ይሆናል ፤ ከታ ላቁ ፡ ባሕር ፡ ወደ ፡ ሖር ፡ ተራራ ፡ ምልክት ፡ ፰ ታመለክታላችሁ ፤ ከሖርም ፡ ተራራ ፡ ወደ ፡ ሐማት ፡ መግቢያ ፡ ምልክት ፡ ታመለክታላችሁ ፡ የዳርቻውም ፡ መውጫ ፡ በጽዳድ ፡ ይሆናል ፤ ፱ ዳርቻውም ፡ ወደ ፡ ዚፍሮን ፡ ያልፋል ፡ እስከ ፡ ሐጸርዔናንም ፡ ድረስ ፡ ይወጣል ፤ ይህ ፡ የሰ ሜን ፡ ዳርቻችሁ ፡ ይሆናል ።

፲ የምሥራቁንም ፡ ዳርቻችሁን ፡ ከሐጸርዔናን ፡ ወደ ፡ ሴፋማ ፡ ምልክት ፡ ታመለክታላችሁ ፤ ፲፩ ዳርቻውም ፡ ከሴፋማ ፡ በዓይን ፡ ምሥራቅ ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ ሪብላ ፡ ይወርዳል ፤ እስከ ፡ ኪኔ ሬት ፡ የባሕር ፡ ወሽመጥ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ፲፪ ይደርሳል ፤ ዳርቻውም ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ይወ ርዳል ÷ መውጫውም ፡ በጨው ፡ ባሕር ፡ ይሆ ናል ። ምድራችሁ ፡ እንደ ፡ ዳርቻዋ ፡ በዙሪያዋ ፡ ይህች ፡ ናት ።

፲፫ ሙሴም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ፡— እግዚአብሔር ፡ ለዘጠኝ ፡ ነገድ ፡ ተኩል ፡ ይሰጡአቸው ፡ ዘንድ ፡ ያዘዘ ፡ በዕጣ ፡ የምትወርሱአት ፡ ምድር ፡ ይህች ፡ ናት ፤ ፲፬ የሮቤልም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ በየአባቶቻቸው ፡ ቤት ÷ የጋድም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ በየአባቶቻ ቸው ፡ ቤት ÷ የምናሴም ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ፲፭ ርስታቸውን ፡ ወርሰዋል ። እነዚህ ፡ ሁለቱ ፡ ነገ ድና ፡ የአንዱ ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ርስታቸውን ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በኢያሪኮ ፡ አንጻር ፡ በምሥ ራቅ ፡ በኩል ፡ ወረሱ ።

፲፮ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፲፯ ተናገረው ፡— ምድሪቱን ፡ ርስት ፡ አድርገው ፡ የሚከፍሉላችሁ ፡ ሰዎች ፡ ስማቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ካህኑ ፡ አልዓዛርና ፡ የነዌ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ። ፲፰ ምድ ሪቱንም ፡ ርስት ፡ አድርገው ፡ ይከፍሉ ፡ ዘንድ ፡ ከየነገዱ ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ አለቃ ፡ ትወስዳላችሁ ። ፲፱ የሰዎቹም ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ከይሁዳ ፡ ነገድ ፡ ፳ የዮፎኒ ፡ ልጅ ፡ ካሌብ ÷ ከስምዖን ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ፳፩ የዓሚሁድ ፡ ልጅ ፡ ሰላሚኤል ÷ ከብንያም ፡ ነገድ ፡ የኪስሎን ፡ ልጅ ፡ ኤልዳድ ÷ ፳፪ ከዳን ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ አንድ ፡ አለቃ ፡ የዮግሊ ፡ ልጅ ፡ ቡቂ ÷ ፳፫ ከዮሴፍም ፡ ልጆች ፡ ከምናሴ ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ አንድ ፡ አለቃ ፡ የሱፊድ ፡ ልጅ ፡ አኒኤል ÷ ፳፬ ከኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ አንድ ፡ አለቃ ፡ የሺ ፍጣን ፡ ልጅ ፡ ቀሙኤል ÷ ፳፭ ከዛብሎን ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ አንድ ፡ አለቃ ፡ የፈርናክ ፡ ልጅ ፡ ኤሊሳ ፈን ÷ ፳፮ ከይሳኮር ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ አንድ ፡ አለቃ ፡ የዖዛ ፡ ልጅ ፡ ፈልጢኤል ÷ ፳፯ ከአሴር ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ አንድ ፡ አለቃ ፡ የሴሎሚ ፡ ልጅ ፡ አሒ ሁድ ÷ ፳፰ ከንፍታሌም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ አንድ ፡ አለቃ ፡ የዓሚሁድ ፡ ልጅ ፡ ፈዳሄል ። ፳፱ እግዚአ ብሔር ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ርስታቸውን ፡ ይከፍሉ ፡ ዘንድ ፡ ያዘዛቸው ፡ እነ ዚህ ፡ ናቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፭ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ በዮርዳኖስ ፡ አጠ ገብ ፡ በኢያሪኮ ፡ አንጻር ፡ በሞዓብ ፡ሜዳ ፡ እን ፪ ዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ሌዋውያን ፡ የሚቀመ ጡባቸውን ፡ ከተሞች ፡ ከርስታቸው ፡ ይሰጡ ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እዘዛቸው ፤ በከ ተሞቹም ፡ ዙሪያ ፡ ያለውን ፡ መሰምርያ ፡ ለሌዋ ውያን ፡ ስጡ ። ፫ እነርሱም ፡ በከተሞቹ ፡ ውስጥ ፡ ይቀመጣሉ ፤ መሰምርያቸውም ፡ ለከብቶቻቸው ፡ ለእንስሶቻቸውም ፡ ለእነርሱም ፡ ላለው ፡ ሁሉ ፡ ይሁን ። ፬ ለሌዋውያንም ፡ የምትሰጡት ፡ የከ

ተማ፡ መሰምርያ፡ በከተማው፡ ዙሪያ፡ ከቅጥሩ፡
ወደ ፡ ውጭ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ ክንድ ፡ ይሁን ።
፭ ከከተማው፡ ውጭ፡ በምሥራቅ፡ በኩል ፡ ሁለት፡
ሺህ ፡ ክንድ ፥ በደቡብ፡ በኩል ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡
ክንድ ፥ በምዕራብ፡ በኩል ፡ ሁለት፡ ሺህ፡ ክንድ፥
በሰሜንም ፡ በኩል ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ክንድ ፡ ትከ
ነዳላችሁ ፥ ከተማውም ፡ በመካከል ፡ ይሆናል ፤
ይህም ፡ የከተሞቹ ፡ መሰምርያ ፡ ይሆንላቸዋል ።
፮ ለሌዋውያንም ፡ የምትሰጡአቸው ፡ ስድስቱ ፡
የመማፀኛ ፡ ከተሞች ፡ ናቸው ፤ እነርሱም ፡ ነፍስ ፡
ገዳይ ፡ ይሸሽባቸው ፡ ዘንድ ፡ የምትሰጡአቸው ፡
ናቸው ፤ ከእነዚህም ፡ ሌላ ፡ አርባ ፡ ሁለት ፡ ከተ
፯ ሞች ፡ ትሰጣላችሁ ። ለሌዋውያን ፡ የምትሰጡ
አቸው ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ አርባ ፡ ስምንት ፡ ከተ
ሞች ፡ ይሆናሉ ፤ ከመሰምርያቸው ፡ ጋር ፡ ትሰ
፰ ጡአቸዋላችሁ ። ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡
ለሌዋውያን ፡ የምትሰጡአቸውን ፡ ከተሞች ፡
እንዲሁ ፡ ስጡ ፤ ከብዙዎቹ ፡ ብዙ ፥ ከጥቂቶቹ ፡
ጥቂት ፡ ትወስዳላችሁ ፤ እያንዳንዱ ፡ እንደ ፡ ወረ
ሱት ፡ እንደ ፡ ርስታቸው ፡ መጠን ፡ ከከተሞቻ
ቸው ፡ ለሌዋውያን ፡ ይሰጣሉ ።

፱ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፲ ተናገረው ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡
ብለህ ፡ ንገራቸው ፡— ወደ ፡ ከነዓን ፡ ምድር ፡ ዮር
፲፩ ዳኖስን ፡ በተሻገራችሁ ፡ ጊዜ ፥ በስሕተት ፡ ነፍስ ፡
የገደለ ፡ ወደዚያ ፡ ይሸሽ ፡ ዘንድ ፡ የመማፀኛ ፡
ከተሞች ፡ እንዲሆኑላችሁ ፡ ከተሞችን ፡ ለእና
፲፪ ንት ፡ ለዩ ። ነፍሰ ፡ ገዳዩ ፡ በማኅበሩ ፡ ፊት ፡ ለፍ
ርድ ፡ እስኪቆም ፡ ድረስ ፡ እንዳይሞት ፥ ከተ
ሞቹ ፡ ከደም ፡ ተበቃይ ፡ የመማፀኛ ፡ ከተሞች ፡
፲፫ ይሁኑላችሁ ። የምትሰጡአቸውም ፡ ስድስቱ ፡
ከተሞች ፡ የመማፀኛ ፡ ከተሞች ፡ ይሁኑላችሁ ።
፲፬ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ሦስት ፡ ከተሞች ፡ ትሰጣላ
ችሁ ፥ በከነዓንም ፡ ምድር ፡ ሦስት ፡ ከተሞች ፡
ትሰጣላችሁ ፤ የመማፀኛ ፡ ከተሞች ፡ ይሆናሉ ።
፲፭ በስሕተት ፡ ነፍስ ፡ የገደለ ፡ ይሸሽበት ፡ ዘንድ ፡
እነዚህ ፡ ስድስት ፡ ከተሞች ፡ ለእስራኤል ፡
ልጆች ፡ በመካከላቸው ፡ ለሚቀመጡ ፡ እንግዶ
ችና ፡ መጻተኞች ፡ መማፀኛ ፡ ይሆናሉ ።

፲፮ በብረት ፡ መሣርያ ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ ቢመ
ታው ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ነው ፤ ነፍሰ ፡ ገዳዩም ፡
፲፯ ፈጽሞ ፡ ይገደል ። ሰውም ፡ በሚሞትበት ፡
በእጁ ፡ ባለው ፡ ድንጋይ ፡ ቢመታው ፡ የተመ
ታውም ፡ ቢሞት ፥ እርሱ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ነው ፤
፲፰ ነፍሰ ፡ ገዳዩም ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደል ። ሰውም ፡
በሚሞትበት ፡ በእጁ ፡ ባለው ፡ በእንጨት ፡
መሣርያ ፡ ቢመታው ፡ የተመታውም ፡ ቢሞት ፥
እርሱ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ነው ፤ ነፍሰ ፡ ገዳዩም ፡
፲፱ ፈጽሞ ፡ ይገደል ። ደም ፡ ተበቃዩ ፡ ራሱ ፡
ነፍሰ ፡ ገዳዩን ፡ ይግደል ፤ ባገኘው ፡ ጊዜ ፡ ይግ
፳ ደለው ። እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ በጥላቻ ፡ ቢደ
ፋው ፥ ወይም ፡ ሸምቆ ፡ አንዳች ፡ ነገር ፡ ቢጥል
፳፩ በት ፥ ወይም ፡ በጥላቻ ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡
በእጁ ፡ ቢመታው ፥ የመታው ፡ ፈጽሞ ፡ ይገ
ደል ፤ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ነው ፤ ደም ፡ ተበቃዩ ፡ ባገ
ኘው ፡ ጊዜ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳዩን ፡ ይግደለው ።

፳፪ ነገር ፡ ግን ፡ ያለ ፡ ጥላቻ ፡ ድንገት ፡ ቢደፋው ፥
ሳይሸምቅም ፡ አንዳች ፡ ነገር ፡ ቢጥልበት ፥
፳፫ ወይም ፡ ሳያየው ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ ሰው ፡ የሚ
ሞትበትን ፡ ድንጋይ ፡ ቢጥልበት ፥ ጠላቱም ፡
ባይሆን ፥ ክፉም ፡ ያደርግበት ፡ ዘንድ ፡ ባይሻ ፥
፳፬ ማኅበሩ ፡ በመቺውና ፡ በደም ፡ ተበቃዩ ፡ መካ
፳፭ ከል ፡ ፍርድን ፡ እንደዚሁ ፡ ይፍረድ ፤ ማኅበ
ሩም ፡ ነፍሰ ፡ ገዳዩን ፡ ከደም ፡ ተበቃዩ ፡ እጅ ፡
ያድነዋል ፥ ማኅበሩም ፡ ወደ ፡ ሸሸበት ፡ ወደ ፡
መማፀኛው ፡ ከተማ ፡ ይመልሰዋል ፤ በቅዱስ ፡
ዘይትም ፡ የተቀባው ፡ ዋነኛው ፡ ካህን ፡ እስኪ
፳፮ ሞት ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ ይቀመጣል ። ነፍሰ ፡
ገዳዩ ፡ ግን ፡ ከሸሸበት ፡ ከመማፀኛው ፡ ከተማ ፡
፳፯ ዳርቻ ፡ ቢወጣ ፥ ደም ፡ ተበቃዩም ፡ ከመማፀ
ኛው ፡ ከተማ ፡ ዳርቻ ፡ ውጭ ፡ ቢያገኘው ፥ ደም ፡
ተበቃዩም ፡ ነፍሰ ፡ ገዳዩን ፡ ቢገድለው ፥ የደም ፡
፳፰ ዕዳ ፡ አይሆንበትም ፤ ዋነኛው ፡ ካህን ፡ እስኪ
ሞት ፡ ድረስ ፡ በመማፀኛው ፡ ከተማ ፡ ውስጥ ፡
መቀመጥ ፡ ይገባው ፡ ነበርና ። ዋነኛው ፡ ካህን ፡
ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ነፍሰ ፡ ገዳዩ ፡ ወደ ፡ ርስቱ ፡
ምድር ፡ ይመለሳል ።

፳፱ እነዚህም ፡ ነገሮች ፡ ለልጅ ፡ ልጃችሁ ፡ በማደሪ
ያችሁ ፡ ሁሉ ፡ ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ ይሁኑላችሁ ።
፴ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ሁሉ ፡ በምስክሮች ፡ አፍ ፡ ይገደ
ላል ፤ በአንድ ፡ ምስክር ፡ ግን ፡ ማናቸውንም ፡
፴፩ ሰው ፡ መግደል ፡ አይገባም ። ሞት ፡ የተፈረደ
በትን ፡ ነፍሰ ፡ ገዳዩንም ፡ ለማዳን ፡ የነፍስ ፡
ዋጋ ፡ አትቀበሉ ፤ እርሱ ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደል ።
፴፪ ዋነኛው ፡ ካህን ፡ ሳይሞት ፡ ወደ ፡ ምድሩ ፡ ይመ
ለስ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መማፀኛው ፡ ከተማ ፡ ከሸ
፴፫ ሸው ፡ የነፍስ ፡ ዋጋ ፡ አትቀበሉ ። ደም ፡ ምድ
ሪቱን ፡ ያረክሳታልና ፡ የምትኖሩባትን ፡ ምድር ፡
አታርክሱአት ፤ በደም ፡ አፍሳሹ ፡ ደም ፡ ካልሆነ ፡
በቀር ፡ ምድሪቱ ፡ ከፈሰሰባት ፡ ደም ፡ አትነጻም ።
፴፬ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካ
ከል ፡ አድራለሁና ፡ የምትኖሩባትን ፡ በመካከል
ዋም ፡ የማድርባትን ፡ ምድር ፡ አታርክሱአት ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፮ ።

፩ ከዮሴፍ ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ የምናሴ ፡ ልጅ ፡
የማኪር ፡ ልጅ ፡ የገለዓድ ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ አለ
ቆች ፡ ቀረቡ ፥ በሙሴና ፡ በእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
፪ አባቶች ፡ አለቆች ፡ ፊት ፡ ተናገሩ ፤ አሉም ፡—
ምድሪቱን ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡ አድ
ርገህ ፡ በዕጣ ፡ ከፍለህ ፡ ትሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ አንተን ፡ ጌታችንን ፡ አዘዘህ ፤ እግ
ዚአብሔርም ፡ የወንድማችንን ፡ የሰለጰዓድን ፡
ርስት ፡ ለሴቶች ፡ ልጆቹ ፡ ትሰጥ ፡ ዘንድ ፡ አን
፫ ተን ፡ ጌታችንን ፡ አዘዘ ። ከሌላም ፡ ከእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ነገድ ፡ ባል ፡ ቢያገቡ ፥ ርስታቸው ፡ ከአ
ባቶቻችን ፡ ርስት ፡ ይነቀላል ፥ እነርሱም ፡ ለሚ
ሆኑበት ፡ ለሌላው ፡ ነገድ ፡ ርስት ፡ ይጨመራል ፤

እንደዚህም ፡ የርስታችን ፡ ዕጣ ፡ ይጐድላል ።
፬፡ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ኢዮቤልዩ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ርስታቸው ፡ ለሚሆኑበት ፡ ነገድ ፡ ርስት ፡ ይጨመራል ፤ እንደዚህም ፡ ርስታቸው ፡ ከአባቶቻችን ፡ ነገድ ፡ ርስት ፡ ይጐድላል ።
፭፡ ሙሴም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ፡— የዮሴፍ ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ በእውነት ፡ ተናገሩ ።
፮፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ሰለጰዓድ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ያዘዘው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የወደዱትን ፡ ያግቡ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከአባታቸው ፡ ነገድ ፡ ብቻ ፡ ያግቡ ።
፯፡ እንደዚህም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡ ከነገድ ፡ ወደ ፡ ነገድ ፡ ምንም ፡ አይተላለፍ ፤ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ አባቶቹ ፡ ነገድ ፡ ርስት ፡ ይጠጋ ።
፰፡ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ የአባቶቹን ፡ ርስት ፡ ይወርስ ፡ ዘንድ ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ ርስት ፡ ያላት ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡ ከአባትዋ ፡ ነገድ ፡ ባል ፡ ታግባ ።
፱፡ እንደዚህም ፡ ከአንድ ፡ ነገድ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ነገድ ፡ ምንም ፡ ርስት ፡ አይተላለፍ ፤ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ርስቱ ፡ ይጠጋ ።
፲፡ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ እንዲሁ ፡ የሰለጰዓድ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ አደረጉ ።
፲፩፡ የሰለጰዓድ ፡ ልጆች ፡ ማህለህ ፥ ቲርጻ ፥ ዔግላ ፥ ሚልካ ፥ ኑዓ ፡ ከአባታቸው ፡ ወንድሞች ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ ተጋቡ ።
፲፪፡ ከዮሴፍ ፡ ልጅ ፡ ከምናሴ ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ ባሎቻቸውን ፡ አገቡ ፥ ርስታቸውም ፡ በአባታቸው ፡ ነገድ ፡ ጸና ።
፲፫፡ እግዚአብሔር ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ በዮርዳኖስ ፡ አጠገብ ፡ በኢያሪኮ ፡ አንጻር ፡ በሞዓብ ፡ ሜዳ ፡ ያዘዛቸው ፡ ትእዛዝና ፡ ፍርድ ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።

# ኦ ሪ ት ፡ ዘ ዳ ግ ም ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፥ በዓረብ ፡ ውስጥ ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ ፊት ፡ ለፊት ፥ በፋራን ፡ በጦፌልም ፡ በላባንም ፡ በሐጼሮትም ፡ በዲዛሃብም ፡ መካከል ፡ ሳሉ ፥ ሙሴ ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ የነገራቸው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ።
፪፡ በሴይር ፡ ተራራ ፡ መንገድ ፡ ከኮሬብ ፡ እስከ ፡ ቃዴስ ፡ በርኔ ፡ ድረስ ፡ የአሥራ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ ነው ።
፫፡ በአርባኛው ፡ ዓመት ፡ በአሥራ ፡ አንደኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፥ ሙሴ ፥ በሐሴቦን ፡ ተቀምጦ ፡ የነበረውን ፡ የአሞራውያንን ፡ ንጉሥ ፡ ሴዎንን ፥ በአስታሮትና ፡ በኤድራይ ፡ ተቀምጦ ፡ የነበረውንም ፡ የባሳንን ፡ ንጉሥ ፡ ዐግን ፡ ከመታ ፡ በኋላ ፥ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ ያዘዘውን ፡ ሁሉ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ነገራቸው ።
፭፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በሞዓብ ፡ ምድር ፡ ሙሴ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ይህችን ፡ ሕግ ፡ ይገልጥ ፡ ጀመር ፡—
፮፡ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ በኮሬብ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረን ፡— በዚህ ፡ ተራራ ፡ የተቀመጣችሁት ፡ በቃ ፤
፯፡ ተመልሳችሁ ፡ ተጓዙ ፤ ወደ ፡ ተራራማው ፡ ወደ ፡ አሞራውያን ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ድንበሮቹም ፡ ሁሉ ፥ በዓረባም ፡ በደጋውም ፡ በቈላውም ፡ በደቡብም ፡ በባሕርም ፡ ዳር ፡ ወዳሉ ፡ ወደ ፡ ከነዓናውያን ፡ ምድር ፥ ወደ ፡ ሊባኖስም ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ወንዝም ፡ እስከ ፡ ኤፍራጥስ ፡ ድረስ ፡ ሂዱ ።
፰፡ እነሆ ፥ ምድሪቱን ፡ በፊታችሁ ፡ አድርጌአለሁ ፤ ግቡ ፥ እግዚአብሔር ፡ ለእነርሱ ፡ ከእነርሱም ፡ በኋላ ፡ ለዘራቸው ፡ ይሰጣት ፡ ዘንድ ፡ ለአባቶቻችሁ ፡ ለአብርሃምና ፡ ለይስሐቅ ፡ ለያዕቆብም ፡ የማለላቸውንም ፡ ምድር ፡ ውረሱ ።
፱፡ በዚያም ፡ ዘመን ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ ተናገርኋችሁ ፡— እኔ ፡ ብቻዬን ፡ ልሸከማችሁ ፡ አልችልም ፤
፲፡ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ አብዝቶአችኋል ፥ እነሆም ፥ እናንተ ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከዋክብት ፡ ብዛት ፡ ናችሁ ።
፲፩፡ የአባቶቻችሁ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡ ቍጥር ፡ ላይ ፡ አልፍ ፡ እእላፋት ፡ ይጨምር ፥ እንደ ፡ ተናገራችሁም ፡ ይባርካችሁ ።
፲፪፡ እኔ ፡ ብቻዬን ፡ ድካማችሁን ፡ ሸክማችሁንም ፡ ክርክራችሁንም ፡ እሸከም ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ እችላለሁ ?
፲፫፡ ከእናንተ ፡ ከየነገዳችሁ ፡ ጥበበኞች ፡ አስተዋዮችም ፡ አዋቂዎችም ፡ የሆኑትን ፡ ሰዎች ፡ ምረጡ ፥ እኔም ፡ በላያችሁ ፡ አለቆች ፡ አደርጋቸዋለሁ ።
፲፬፡ እናንተም ፡— እናደርገው ፡ ዘንድ ፡ የተናገርኸው ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ መልካም ፡ ነው ፡ ብላችሁ ፡ መለሳችሁልኝ ።
፲፭፡ ጥበበኞችና ፡ አዋቂዎች ፡ የሆኑትን ፡ የነገዶቻችሁን ፡ አለቆች ፡ መረጥሁ ፥ በእናንተም ፡ ላይ ፡ አለቆች ፡ የሻለቆችም ፡ የመቶ ፡ አለቆችም ፡ የአምሳ ፡ አለቆችም ፡ የአሥር ፡ አለቆችም ፡ ገዦችም ፡ በየነገዶቻቸው ፡ አደረግኋቸው ።
፲፮፡ በዚያን ፡ ጊዜም ፡— የወንድሞቻችሁን ፡ ነገር ፡ ስሙ ፤ በሰውና ፡ በወንድሙ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ባለው ፡ መጻተኛ ፡ መካከል ፡ በጽድቅ ፡ ፍረዱ ።
፲፯፡ በፍርድም ፡ አድልዎ ፡ አታድርጉ ፤ ታላቁን ፡ እንደምትሰሙ ፥ ታናሹንም ፡ እንዲሁ ፡ ስሙ ፤ ፍርድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ነውና ፡ ከሰው ፡ ፊት ፡ አትፍሩ ፤ ከነገርም ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ቢከብዳችሁ ፡ እርሱን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አምጡት ፥ እኔም ፡ እሰማዋለሁ ፡ ብዬ ፡ ፈራጆቻችሁን ፡ አዘዝኋቸው ።
፲፰፡ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ልታደርጉት ፡ የሚገባችሁን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አዘዝኋችሁ ።

እንደዚህም ፡ የርስታችን ፡ ዕጣ ፡ ይጐድላል ። ፬ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ኢዮቤልዩ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ርስታቸው ፡ ለሚሆኑበት ፡ ነገድ ፡ ርስት ፡ ይጨመራል ፤ እንደዚህም ፡ ርስታቸው ፡ ከአባቶቻችን ፡ ነገድ ፡ ርስት ፡ ይጐድላል ።

፭ ሙሴም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ፡— የዮሴፍ ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ በእውነት ፡ ፮ ተናገሩ ። እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ሰለጰዓድ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ያዘዘው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የወደዱትን ፡ ያግቡ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከአባታቸው ፡ ፯ ነገድ ፡ ብቻ ፡ ያግቡ ። እንደዚህም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡ ከነገድ ፡ ወደ ፡ ነገድ ፡ ምንም ፡ አይተላለፍ ፤ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ አባቶቹ ፡ ነገድ ፡ ርስት ፡ ፰ ይጠጋ ። ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ የአባቶቹን ፡ ርስት ፡ ይወርስ ፡ ዘንድ ፥ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ ርስት ፡ ያላት ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡ ከአባትዋ ፡ ነገድ ፡ ባል ፡ ታግባ ። ፱ እንደዚህም ፡ ከአንድ ፡ ነገድ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ነገድ ፡ ምንም ፡ ርስት ፡ አይተላለፍ ፤ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ርስቱ ፡ ይጠጋ ።

፲ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ እንዲሁ ፡ የሰለጰዓድ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ አደረጉ ። ፲፩ የሰለጰዓድ ፡ ልጆች ፡ ማህለህ ፥ ቲርጻ ፥ ዔግላ ፥ ሚልካ ፥ ኑዓ ፡ ከአባታቸው ፡ ወንድሞች ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ ተጋቡ ። ፲፪ ከዮሴፍ ፡ ልጅ ፡ ከምናሴ ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ ባሎቻቸውን ፡ አገቡ ፥ ርስታቸውም ፡ በአባታቸው ፡ ነገድ ፡ ጸና ።

፲፫ እግዚአብሔር ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ በዮርዳኖስ ፡ አጠገብ ፡ በኢያሪኮ ፡ አንጻር ፡ በሞዓብ ፡ ሜዳ ፡ ያዘዛቸው ፡ ትእዛዝና ፡ ፍርድ ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።

# ኦ ሪ ት ፡ ዘ ዳ ግ ም ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፥ በዓረብ ፡ ውስጥ ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ ፊት ፡ ለፊት ፥ በፋራን ፡ በጦፌልም ፡ በላባንም ፡ በሐጼሮትም ፡ በዲዛሃብም ፡ መከከል ፡ ሳሉ ፥ ሙሴ ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ የነገራቸው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። ፪ በሴይር ፡ ተራራ ፡ መንገድ ፡ ከኮሬብ ፡ እስከ ፡ ቃዴስ ፡ በርኔ ፡ ድረስ ፡ የአሥራ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ፫፡፬ መንገድ ፡ ነው ። በአርበኛው ፡ ዓመት ፡ በአሥራ ፡ አንደኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፥ ሙሴ ፥ በሐሴቦን ፡ ተቀምጦ ፡ የነበረውን ፡ የአሞራውያንን ፡ ንጉሥ ፡ ሴዎንን ፥ በአስታሮትና ፡ በኤድራይ ፡ ተቀምጦ ፡ የነበረውንም ፡ የባሳንን ፡ ንጉሥ ፡ ዐግን ፡ ከመታ ፡ በኋላ ፥ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ ያዘዘውን ፡ ፭ ሁሉ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ነገራቸው ። በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በሞዓብ ፡ ምድር ፡ ሙሴ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ይህችን ፡ ሕግ ፡ ይገልጥ ፡ ጀመር ፡—

፮ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ በኮሬብ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረን ፡— በዚህ ፡ ተራራ ፡ የተ ፯ ቀመጣችሁት ፡ በቃ ፤ ተመልሳችሁ ፡ ተጓዙ ፤ ወደ ፡ ተራራማው ፡ ወደ ፡ አሞራውያን ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ድንበሮቹም ፡ ሁሉ ፥ በዓረባም ፡ በደጋውም ፡ በቈላውም ፡ በደቡብም ፡ በባሕርም ፡ ዳር ፡ ወዳሉ ፡ ወደ ፡ ከነዓናውያን ፡ ምድር ፥ ወደ ፡ ሊባኖስም ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ወንዝም ፡ እስከ ፡ ፰ ኤፍራጥስ ፡ ድረስ ፡ ሂዱ ። እነሆ ፥ ምድሪቱን ፡ በፊታችሁ ፡ አድርጌአለሁ ፤ ግቡ ፥ እግዚአብሔር ፡ ለእነርሱ ፡ ከእነርሱም ፡ በኋላ ፡ ለዘራቸው ፡ ይሰጣት ፡ ዘንድ ፡ ለአባቶቻችሁ ፡ ለአብርሃምና ፡ ለይስሐቅ ፡ ለያዕቆብም ፡ የማለላቸውንም ፡ ምድር ፡ ውረሱ ።

፱ በዚያም ፡ ዘመን ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ ተናገርኋችሁ ፡— እኔ ፡ ብቻዬን ፡ ልሸከማችሁ ፡ አልችልም ፤ ፲ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ አብዝቶ ፡ አችኋል ፥ እነሆም ፥ እናንተ ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከዋክብት ፡ ብዛት ፡ ናችሁ ። ፲፩ የአባቶቻችሁ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡ ቍጥር ፡ ላይ ፡ እልፍ ፡ እእላፋት ፡ ይጨምር ፥ እንደ ፡ ተናገራችሁም ፡ ይባርካችሁ ። ፲፪ እኔ ፡ ብቻዬን ፡ ድካማችሁን ፡ ሸክማችሁንም ፡ ክርክራችሁንም ፡ እሸከም ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ እችላለሁ ? ፲፫ ከእናንተ ፡ ከየነገዳችሁ ፡ ጥበበኞች ፡ አስተዋዮችም ፡ አዋቂዎችም ፡ የሆኑትን ፡ ሰዎች ፡ ምረጡ ፥ እኔም ፡ በላያችሁ ፡ አለቆች ፡ አደርጋቸዋለሁ ። ፲፬ እናንተም ፡— እናደርገው ፡ ዘንድ ፡ የተናገርኸው ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ መልካም ፡ ነው ፡ ብላችሁ ፡ መለሳችሁልኝ ። ፲፭ ጥበበኞችና ፡ አዋቂዎች ፡ የሆኑትን ፡ የነገዶቻችሁን ፡ አለቆች ፡ መረጥሁ ፥ በእናንተም ፡ ላይ ፡ አለቆች ፡ የሻለቆችም ፡ የመቶ ፡ አለቆችም ፡ የአምሳ ፡ አለቆችም ፡ የአሥር ፡ አለቆችም ፡ ገዦችም ፡ በየነገዶቻቸው ፡ አደረግኋቸው ። ፲፮ በዚያን ፡ ጊዜም ፡— የወንድሞቻችሁን ፡ ነገር ፡ ስሙ ፤ በሰውና ፡ በወንድሙ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ባለው ፡ መጻተኛ ፡ መከከል ፡ በጽድቅ ፡ ፍረዱ ። ፲፯ በፍርድም ፡ አድልዎ ፡ አታድርጉ ፤ ታላቁን ፡ እንደምትሰሙ ፥ ታናሹንም ፡ እንዲሁ ፡ ስሙ ፤ ፍርድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ነውና ፡ ከሰው ፡ ፊት ፡ አትፍሩ ፤ ከነገርም ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ቢከብዳችሁ ፡ እርሱን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አምጡት ፥ እኔም ፡ እሰማዋለሁ ፡ ብዬ ፡ ፈራጆቻችሁን ፡ አዘዝኋቸው ። ፲፰ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ልታደርጉት ፡ የሚገባችሁን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አዘዝኋችሁ ።

፲፱ ከኮሬብም ፡ ተጓዝን ÷ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘን ፡ በታላቁ ፡ እጅግም ፡ በሚያስፈራ ፡ በዚያ ፡ ባያችሁት ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሁሉ ፡ በኩል ፡ በተራራማው ፡ በአሞራውያን ፡ መንገድ ፡ ሄድን ፤ ወደ ፡ ቃዴስ ፡ በርኔም ፡ መጣን ። ፳ እኔም ፡— አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደሚሰጠን ፡ ወደ ፡ ተራራማው ፡ ወደ ፡ አሞራውያን ፡ ፳፩ አገር ፡ መጣችሁ ፤ እነሆ ÷ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምድሪቱን ፡ በፊትህ ፡ አድርጎአል ፤ የአባቶችህ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳለህ ÷ ውጣ ÷ ውረሳት ፤ አትፍራ ÷ አትደንግጥም ፡ ፳፪ አልኋችሁ ። እናንተም ፡ ሁላችሁ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ቀርባችሁ ፡— ምድሪቱን ፡ እንዲጐበኙልንና ፡ እንወጣበት ፡ ዘንድ ፡ የሚገባንን ፡ የመንገዱንና ፡ የምንገባባቸውን ፡ የእነዚያን ፡ ከተሞች ፡ ወሬ ፡ ተመልሰው ፡ እንዲነግሩን ፡ በፊታችን ፡ ሰዎች ፡ ፳፫ እንስደድ ፡ አላችሁኝ ። ያም ፡ ነገር ፡ ደስ ፡ አሰኘኝ ፤ ከእናንተም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሰው ፡ መረጥሁ ፤ ከየነገዱ ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ፳፬ ነበረ ። ሄዱም ÷ ወደ ፡ ተራራማውም ፡ ወጡ ÷ ወደ ፡ ኤሽኮልም ፡ ሸለቆ ፡ መጥተው ፡ ጐበኙ ፳፭ አት ። ከምድሪቱም ፡ ፍሬ ፡ በእጃቸው ፡ ወሰዱ ÷ ወደ ፡ እኛም ፡ ይዘውት ፡ መጡ ፡— አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚሰጠን ፡ ምድር ፡ መልካም ፡ ናት ፡ ብለውም ፡ አወሩልን ።

፳፮ በአምላካችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ ላይ ፡ ዐመፃችሁ ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ መው ፳፯ ጣትን ፡ እንቢ ፡ አላችሁ ፤ በድንኳናችሁም ፡ ውስጥ ፡ እንዲህ ፡ እያላችሁ ፡ አጕረመረማችሁ ፡— እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ጠላን ፡ እንዲያጠፋን ፡ በአሞራውያን ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጠን ፡ ዘንድ ፡ ፳፰ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ አወጣን ። ወዴት ፡ እንወጣለን ? ሕዝቡ ፡ ብዙ ፡ ነው ÷ ቁመቱም ፡ ከእኛ ፡ ይረዝማል ÷ ከተሞቹም ፡ ታላላቆች ፡ የተመሸጉም ፡ እስከ ፡ ሰማይም ፡ የደረሱ ፡ ናቸው ÷ የዔናቅንም ፡ ልጆች ፡ ደግሞ ፡ በዚያ ፡ አየናቸው ፡ ብለው ፡ ወንድሞቻችን ፡ ልባችንን ፡ አስፈሩት ። ፳፱ እኔም ፡ አልኋችሁ ፡— አትደንግጡ ÷ ከእነርሱም ፡ አትፍሩ ፤ ፴ በፊታችሁ ፡ የሚሄደው ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ÷ እናንተ ፡ ስታዩ ፡ በግብፅና ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንዳደረገላችሁ ፡ ፴፩ ሁሉ ÷ ስለ ፡ እናንተ ፡ ይዋጋል ፤ ወደዚህም ፡ ስፍራ ፡ እስክትመጡ ፡ ድረስ ፡ በሄዳችሁበት ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ÷ ሰው ፡ ልጁን ፡ እንዲሸከም ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተሸከመህ ፡ ፴፪ ፴፫ አንተ ፡ አይተሃል ። ዳሩ ፡ ግን ፡ ለሰፈራችሁ ፡ የሚገባውን ፡ ስፍራ ፡ እንዲፈልግላችሁ ÷ ትሄዱበት ፡ ዘንድ ፡ የሚገባውንም ፡ መንገድ ፡ እንዲያሳያችሁ ፡ ሌሊት ፡ በእሳት ÷ ቀን ፡ በደመና ፡ በፊታችሁ ፡ በመንገድ ፡ ሲሄድ ፡ የነበረውን ፡ አምላካችሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ አላመናችሁም ።

፴፬ እግዚአብሔርም ፡ የቃላችሁን ፡ ድምፅ ፡ ፴፭ ሰምቶ ፡ ተቈጣ ፡— ለአባቶቻችሁ ፡ እሰጣት ፡ ዘንድ ፡ የማልሁላቸውን ፡ መልካሚቱን ፡ ምድር ፡ ከእነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ከዚህ ፡ ክፉ ፡ ትውልድ ፡ ፴፮ ማንም ፡ አያይም ÷ ከዮፎኒ ፡ ልጅ ፡ ከካሌብ ፡ በቀር ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ ያያታል ፤ እግዚአብሔርን ፡ ፈጽሞ ፡ ተከትሎአልና ፡ የረገጣትን ፡ ምድር ፡ ለእርሱ ፡ ለልጆቹም ፡ እሰጣለሁ ፡ ብሎ ፡ ማለ ። ፴፯ እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፡ በእናንተ ፡ ምክንያት ፡ በእኔ ፡ ተቈጣ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡— አንተ ፡ ደግሞ ፡ ፴፰ ወደዚያ ፡ አትገባም ፤ በፊትህ ፡ የሚቆም ፡ የነዌ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡ እርሱ ፡ ወደዚያ ፡ ይገባል ፤ እርሱ ፡ ለእስራኤል ፡ ምድሪቱን ፡ ያወርሳልና ፡ አደፋፍረው ። ፴፱ ደግሞ ፡— ለምርኮ ፡ ይሆናሉ ፡ ያላችኋቸው ፡ ሕፃናቶቻችሁ ÷ ዛሬም ፡ መልካሙን ፡ ከክፉ ፡ መለየት ፡ የማይችሉ ፡ ልጆቻችሁ ÷ እነርሱ ፡ ወደዚያ ፡ ይገባሉ ÷ ምድሪቱንም ፡ ለእነርሱ ፡ እሰጣለሁ ፡ ይወርሱአታልም ። ፵ እናንተ ፡ ግን ፡ ተመልሳችሁ ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሂዱ ።

፵፩ እናንተም ፡— እግዚአብሔርን ፡ በድለናል ፤ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘን ፡ ሁሉ ፡ እንወጣለን ÷ እንዋጋለን ፡ ብላችሁ ፡ መለሳችሁልኝ ። ከእናንተም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የጦር ፡ መሣሪያውን ፡ ያዘ ÷ ወደ ፡ ተራራማውም ፡ አገር ፡ መውጣትን ፡ አቀለላችሁት ። ፵፪ እግዚአብሔርም ፡— እኔ ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡ አይደለሁምና ፡ በጠላቶቻችሁ ፡ ፊት ፡ እንዳትወድቁ ፡ አትውጡ ÷ አትዋጉም ፡ በላቸው ፡ አለኝ ። ፵፫ እኔም ፡ ተናገርኋችሁ ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ ላይ ፡ ዐመፃችሁ ፡ እንጂ ፡ አልሰማችሁም ፤ በትዕቢታችሁም ፡ ወደ ፡ ተራ ፵፬ ራማው ፡ አገር ፡ ወጣችሁ ። በዚያም ፡ በተራራማው ፡ አገር ፡ ይኖሩ ፡ የነበር ፡ አሞራውያን ፡ ወጥተው ፡ ተጋጠሙአችሁ ÷ ንብ ፡ እንደምታሳድድም ፡ አሳደዱአችሁ ÷ እስከ ፡ ሔርማም ፡ ፵፭ ድረስ ፡ በሴይር ፡ መቱአችሁ ። ተመልሳችሁም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አለቀሳችሁ ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ድምፃችሁን ፡ አልሰማም ÷ ፵፮ ወደ ፡ እናንተም ፡ አላዳመጠም ። እንደ ፡ ተቀመጣችሁበትም ፡ ዘመን ፡ መጠን ፡ በቃዴስ ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ ተቀመጣችሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ እንዳለኝ ፡ ተመልሰን ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሄድን ፤ የሴይርንም ፡ ተራራ ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ ፪ ዞርን ። እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተና ፫ ገረኝ ፡— ይህን ፡ ተራራ ፡ መዞር ፡ ይበቃችኋል ፤ ፬ ተመልሳችሁ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ሂዱ ። ሕዝቡንም ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ እዘዛቸው ፡— በሴይር ፡ ላይ ፡ በተቀመጡት ፡ በወንድሞቻችሁ ፡ በዔሳው ፡ ልጆች ፡ አገር ፡ ታልፉላችሁ ÷ እነርሱም ፡ ይፈሩአችኋል ፤ እንግዲህ ፡ እጅግ ፡ ተጠንቀቁ ። ፭ የሴይርን ፡ ተራራ ፡ ለዔሳው ፡ ርስት ፡ አድርጌ ፡ ስለ ፡ ሰጠሁ ፡ እኔ ፡ ከምድራቸው ፡ የጫማ ፡

መርገጫ ፡ ታህል ፡ እንኳ ፡ አልሰጣችሁምና ፡
፮፤ አትጣሉአቸው ። ከእነርሱ ፡ በገንዘብ ፡ ምግብ ፡
ገዝታችሁ ፡ ትበላላችሁ ፤ ውኃም ፡ ደግሞ ፡ በገ
፯፤ ንዘብ ፡ ገዝታችሁ ፡ ትጠጣላችሁ ። አምላክህ ፡
እግዚአብሔር ፡ የእጅህን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ባርከ
ልሃልና ፤ በዚህ ፡ በታላቅ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ መሄ
ድህን ፡ አውቆአል ፤ በዚህ ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡
ውስጥ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡
፰፤ ጋር ፡ ነበረ ፥ አንዳችም ፡ አላጣህም ። በሴይ
ርም ፡ ከተቀመጡት ፡ ከወንድሞቻችን ፡ ከዔ
ሳው ፡ ልጆች ፡ በዓረባ ፡ መንገድ ፡ ከኤላትና ፡
ከዔጽዮንጋብር ፡ አለፍን ።
ተመልሰንም ፡ በሞዓብ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ መን
፱፤ ገድ ፡ አለፍን ። እግዚአብሔርም ፡ አለኝ ፡—
እኔ ፡ ዔርን ፡ ለሎጥ ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡ አድርጌ ፡
ስለ ፡ ሰጠሁ ፡ ከምድሩ ፡ ርስት ፡ አልሰጣችሁ
ምና ፡ ሞዓብን ፡ አትጣላ ፡ በሰልፍም ፡ አትው
፲፤ ጋቸው ። አስቀድሞ ፡ ታላቅና ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡
እንደ ፡ ዔናቅም ፡ ልጆች ፡ በቁመት ፡ የረዘሙ ፡
፲፩፤ ኤሚማውያን ፡ በዚያ ፡ ይቀመጡ ፡ ነበር ። እነ
ርሱም ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ዔናቅ ፡ ልጆች ፡ ራፋ
ይም ፡ ይባሉ ፡ ነበር ፤ ሞዓባውያን ፡ ግን ፡
፲፪፤ ኤሚም ፡ ይሉአቸዋል ። ሖራውያንም ፡ ደግሞ ፡
አስቀድሞ ፡ በሴይር ፡ ላይ ፡ ተቀምጠው ፡ ነበር ፥
የዔሳው ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ አሳደዱአቸው ፤ እግ
ዚአብሔርም ፡ በሰጠው ፡ በርስቱ ፡ ምድር ፡
እስራኤል ፡ እንዳደረገ ፥ ከፊታቸው ፡ አጠፉአ
፲፫፤ ቸው ፥ በስፍራቸውም ፡ ተቀመጡ ። እግዚአ
ብሔርም ፡— ተነሡ ፡ የዘሬድንም ፡ ፈፋ ፡ ተሻ
፲፬፤ ገሩ ፡ አለ ። የዘሬድንም ፡ ፈፋ ፡ ተሻገርን ። የዘ
ሬድንም ፡ ፈፋ ፡ እስከ ፡ ተሻገርንበት ፡ ድረስ ፥
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ማለባቸው ፡ የሰልፈ
ኞች ፡ ትውልድ ፡ ሁሉ ፡ ከሰፈሩ ፡ መካከል ፡
እስከ ፡ ጠፉ ፡ ድረስ ፥ ከቃዴስ ፡ በርኔ ፡ የተጓዝን
በት ፡ ዘመን ፡ ሠላሳ ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ።
፲፭፤ ከሰፈርም ፡ መካከል ፡ ተቈርጠው ፡ እስኪጠፉ ፡
ድረስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ በላያቸው ፡ ነበረ ።
፲፮፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ሰልፈኞቹ ፡ ከጠፉ ፡ ከሕዝ
፲፯፤ ቡም ፡ መካከል ፡ ከሞቱ ፡ በኋላ ፥ እግዚአብሔር ፡
፲፰፤ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረኝ ፡— አንተ ፡ ዛሬ ፡ የሞ
፲፱፤ ዓብን ፡ ዳርቻ ፡ ዔርን ፡ ታልፋለህ ፤ ለሎጥም ፡
ልጆች ፡ ርስት ፡ አድርጌ ፡ ስለ ፡ ሰጠሁ ፡ ከአሞን ፡
ልጆች ፡ ምድር ፡ ርስት ፡ አልሰጥህምና ፡ በአ
ሞን ፡ ልጆች ፡ አቅራቢያ ፡ ስትደርስ ፡ አትጣላ
፳፤ ቸው ፡ አትውጋቸውም ። ያም ፡ ደግሞ ፡ የራ
ፋይም ፡ ምድር ፡ ተብሎ ፡ ተቈጠረ ፤ ራፋይ
ምም ፡ አስቀድሞ ፡ በዚያ ፡ ተቀምጠው ፡ ነበር ፤
አሞናውያን ፡ ግን ፡ ዘምዙማውያን ፡ ብለው ፡
፳፩፤ ይጠሩአቸዋል ። ታላቅና ፡ ብዙም ፡ ሕዝብ ፡
እንደ ፡ ዔናቅም ፡ ልጆች ፡ ቁመታቸው ፡ የረ
ዘመ ፡ ነበሩ ፤ እግዚአብሔር ፡ ከፊታቸው ፡ አጠ
ፋቸው ፤ እነርሱንም ፡ አሳድደው ፡ በስፍራቸው ፡
፳፪፤ ተቀመጡ ። ሖራውያንን ፡ ከፊታቸው ፡ አጥ
ፍቶ ፡ በሴይር ፡ ለተቀመጡት ፡ ለዔሳው ፡ ልጆች ፡
እንዳደረገ ፡ እንዲሁ ፡ ለእነርሱ ፡ አደረገ ፤ እነር
ሱንም ፡ አሳድደው ፡ በስፍራቸው ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡
፳፫፤ ድረስ ፡ ተቀመጡ ። እስከ ፡ ጋዛም ፡ ድረስ ፡ በመ
ንደሮች ፡ ተቀምጠው ፡ የነበሩትን ፡ ኤዋውያ
ንን ፡ ከከፍቶር ፡ የወጡ ፡ ከፍቶራውያን ፡ አጠ
፳፬፤ ፉአቸው ፥ በስፍራቸውም ፡ ተቀመጡ ። ደግ
ሞም ፡ አለ ፡— ተነሥታችሁ ፡ ሂዱ ፥ የአርኖን
ንም ፡ ሸለቆ ፡ ተሻገሩ ፤ እነሆ ፥ አሞራዊውን ፡
የሐሴቦንን ፡ ንጉሥ ፡ ሴዎንን ፡ ምድሩንም ፡ በእ
ጅህ ፡ አሳልፌ ፡ ሰጥቼሃለሁ ፤ እርስዋን ፡ በመ
፳፭፤ ውረስ ፡ ጀምር ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ተዋጋ ። ከሰ
ማይ ፡ በታች ፡ ባሉ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ማስ
ደንገጥህንና ፡ ማስፈራትህን ፡ እሰድድ ፡ ዘንድ ፡
ዛሬ ፡ እጀምራለሁ ፤ ወሬህን ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡
በፊትህ ፡ ይንቀጠቀጣሉ ፥ ድንጋጤም ፡ ይይዛ
ቸዋል ።
፳፮፤ ከቅዴሞትም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ የሰላምን ፡ ቃል ፡
ይነግሩት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ሐሴቦን ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡
ሴዎን ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ መልእክተኞችን ፡
፳፯፤ ላክሁ ፡— በአገርህ ፡ ላይ ፡ ልለፍ ፤ በአውራ ፡
ጐዳና ፡ እሄዳለሁ ፥ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡
፳፰፡፳፱፤ አልተላለፍም ። የምበላውን ፡ ምግብ ፡ በገን
ዘብ ፡ ሽጥልኝ ፥ የምጠጣውንም ፡ ውኃ ፡ በገን
ዘብ ፡ ስጠኝ ፤ በሴይር ፡ የተቀመጡ ፡ የዔሳው ፡
ልጆች ፡ በዔርም ፡ የተቀመጡ ፡ ሞዓባውያን ፡
እንዳደረጉልኝ ፥ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡
ወደሚሰጠን ፡ ምድር ፡ ዮርዳኖስን ፡ እስክሻገር ፡
፴፤ ድረስ ፡ ብቻ ፡ በእግሬ ፡ ልለፍ ። የሐሴቦን ፡
ንጉሥ ፡ ሴዎን ፡ ግን ፡ ያሳልፈን ፡ ዘንድ ፡ አልፈ
ቀደም ፤ እንደ ፡ ዛሬው ፡ ሁሉ ፡ በእጅህ ፡ አሳ
ልፎ ፡ ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ መንፈሱን ፡ አደንድኖታልና ፥ ልቡንም ፡
፴፩፤ አጽንቶታልና ። እግዚአብሔርም ፡— ሴዎንንና ፡
ምድሩን ፡ በእጅህ ፡ አሳልፌ ፡ መስጠት ፥ እነሆ ፥
ጀመርሁ ፤ ምድሩን ፡ ትገዛት ፡ ዘንድ ፡ መውረስ ፡
፴፪፤ ጀምር ፡ አለኝ ። ሴዎንም ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ሊጋ
፴፫፤ ጠሙን ፡ ወደ ፡ ያህጽ ፡ ወጡ ። አምላካችንም ፡
እግዚአብሔር ፡ እርሱን ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠን ፤ እር
ሱንም ፡ ልጆቹንም ፡ ሕዝቡንም ፡ ሁሉ ፡ መታን ።
፴፬፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ከተሞቹን ፡ ሁሉ ፡ ወሰድን ፡
የተቀመጡባቸውንም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ሴቶች
ንም ፡ ሕፃናቶችንም ፡ አጠፋን ፤ አንዳችም ፡ አላ
፴፭፤ ስቀረንም ፥ ከብቶቻቸውንና ፡ ከከተሞቻቸው ፡
ያገኘነውን ፡ ብዝበዛ ፡ ለራሳችን ፡ ወሰድን ፡ እንጂ ።
፴፮፤ በአርኖን ፡ ቈላ ፡ አጠገብ ፡ካለችው ፡ ከአሮዔር ፡
ከሸለቆውም ፡ ውስጥ ፡ ካለችው ፡ ከተማ ፡ ጀም
ረን ፡ እስከ ፡ ገለዓድ ፡ ድረስ ፡ ማናቸይቱም ፡
ከተማ ፡ አልጠነከረችብንም ፤ አምላካችን ፡ እግ
፴፯፤ ዚአብሔር ፡ ሁሉን ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠን ። ዳሩ ፡
ግን ፡ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ከለ
ከለን ፡ ሁሉ ፥ ወደ ፡ አሞን ፡ ልጆች ፡ ምድር ፡
በያቦቅም ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ ወዳለው ፡ ስፍራ ፡
ሁሉ ፡ በተራራማውም ፡ አገር ፡ ወዳሉት ፡ ከተ
ሞች ፡ አልደረስንም ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ተመልሰን ፡ በባሳን ፡ መንገድ ፡ ወጣን ፥ የባሳን ፡ ንጉሥ ፡ ዐግም ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በኤድራይ ፡ ሊዋጉን ፡ ወጡ ። ፪ እግዚአብሔርም ፡— እርሱንና ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ምድሩንም ፡ በእጅህ ፡ አሳልፌ ፡ ሰጥቼሃለሁና ፡ አትፍራው ፤ በሐሴቦን ፡ ይኖር ፡ በነበረው ፡ በአሞራውያን ፡ ንጉሥ ፡ በሴዎን ፡ ላይ ፡ እንዳደረግህ ፡ በእርሱም ፡ ታደርግበታለህ ፡ አለኝ ። ፫ አምላካችን ፡ እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፡ የባሳንን ፡ ንጉሥ ፡ ዐግን ፡ ሕዝቡንም ፡ ሁሉ ፡ በእጃችን ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠን ፤ እኛም ፡ መታነው ፤ አንድ ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ አምልጦ ፡ አልቀረለትም ። ፬ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ከተሞቹን ፡ ሁሉ ፡ ወሰድን ፤ አንድም ፡ ያልወሰድነው ፡ የለም ፤ በባሳን ፡ ያለውን ፡ የዐግን ፡ መንግሥት ፥ የአርጎብን ፡ አገር ፡ ሁሉ ፥ ስድሳ ፡ ከተሞችን ፡ ወሰድን ። ፭ በቅጥር ፡ ከልተመሸጉት ፡ ከእጅግ ፡ ብዙ ፡ ከተሞች ፡ ሌላ ፥ እነዚህ ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ቁመቱ ፡ ረጅም ፡ በሆነ ፡ ቅጥር ፡ በመዝጊያና ፡ በመወርወሪያም ፡ የተመሸጉ ፡ ነበሩ ። ፮ በሐሴቦንም ፡ ንጉሥ ፡ በሴዎን ፡ እንዳደረግን ፡ ፈጽሞ ፡ አጠፋናቸው ፤ ከተሞቹን ፡ ሁሉ ፡ ከወንዶችና ፡ ከሴቶች ፡ ከሕፃናቶችም ፡ ጋር ፡ አጠፋናቸው ። ፯ ከብቶቹን ፡ ሁሉ ፡ የከተሞቹንም ፡ ምርኮ ፡ ለእኛ ፡ በዘበዝን ።

፰ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ከአርኖን ፡ ሸለቆ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አርሞንዔም ፡ ተራራ ፡ ድረስ ፡ ምድሪቱን ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ከነበሩ ፡ ከሁለቱ ፡ ከአሞራውያን ፡ ነገሥታት ፡ እጅ ፡ ወሰድን ፤ ፱ ሲዶናውያን ፡ አርሞንዔምን ፡ ሢርዮን ፡ ብለው ፡ ይጠሩታል ፥ አሞራውያንም ፡ ሳኔር ፡ ብለው ፡ ይጠሩታል ። ፲ በሜዳው ፡ ያሉትን ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፥ ገለዓድንም ፡ ሁሉ ፥ በባሳንም ፡ ያሉትን ፡ የዐግን ፡ መንግሥት ፡ ከተሞች ፡ እስከ ፡ ሰልካና ፡ እስከ ፡ ኤድራይ ፡ ድረስ ፡ ባሳንን ፡ ሁሉ ፡ ወሰድን ። ፲፩ ከራፋይም ፡ ወገን ፡ የባሳን ፡ ንጉሥ ፡ ዐግ ፡ ብቻውን ፡ ቀርቶ ፡ ነበር ፤ እነሆ ፥ አልጋው ፡ የብረት ፡ አልጋ ፡ ነበረ ፤ እርሱ ፡ በአሞን ፡ ልጆች ፡ አገር ፡ በረባት ፡ አለ ፤ ርዝመቱ ፡ ዘጠኝ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ አራት ፡ ክንድ ፡ በሰው ፡ ክንድ ፡ ልክ ፡ ነበረ ። ፲፪ ይህችንም ፡ ምድር ፡ በዚያን ፡ ዘመን ፡ ወረስን ፤ በአርኖንም ፡ ሸለቆ ፡ አጠገብ ፡ ካለችው ፡ ከአሮዔር ፡ ጀምሮ ፡ የገለዓድን ፡ ተራራማ ፡ አገር ፡ እኩሌታ ፡ ከተሞቹንም ፡ ለሮቤልና ፡ ለጋድ ፡ ነገድ ፡ ሰጠኋቸው ። ፲፫ ከገለዓድም ፡ የቀረውን ፡ የዐግንም ፡ መንግሥት ፡ ባሳንን ፡ ሁሉ ፥ የአርጎብንም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ለምናሴ ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ሰጠሁ ፤ ያችም ፡ ባሳን ፡ ሁሉ ፡ የራፋይም ፡ አገር ፡ ተብላ ፡ ተቈጠረች ። ፲፬ የምናሴ ፡ ልጅ ፡ ኢያዕር ፡ እስከ ፡ ጌሹራውያንና ፡ እስከ ፡ ማዕካታውያን ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ የአርጎብን ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ወሰደ ፤ ይህችንም ፡ የባሳንን ፡ ምድር ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በስሙ ፡ የኢያዕር ፡ መንደሮች ፡ ብሎ ፡ ጠራ ። ፲፭ ለማኪርም ፡ ገለዓድን ፡ ሰጠሁት ። ፲፮ ለሮቤል ፡ ነገድና ፡ ለጋድም ፡ ነገድ ፡ ከገለዓድ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አርኖን ፡ ሸለቆ ፡ ድረስ ፡ የሸለቆውን ፡ እኩሌታ ፡ ዳርቻውንም ፥ እስከ ፡ አሞን ፡ ልጆች ፡ ዳርቻ ፡ እስከ ፡ ያቦቅ ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ፥ ፲፯ ከኪኔሬት ፡ እስከ ፡ ዓረባ ፡ ባሕር ፡ እርሱም ፡ የጨው ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፡ ከፈስጋ ፡ ተራራ ፡ በታች ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ያለውን ፡ ዓረባ ፡ ዮርዳኖስንም ፡ ዳሩንም ፡ ሰጠኋቸው ።

፲፰ በዚያም ፡ ዘመን ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ አዘዝኋችሁ ፡— አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይህችን ፡ ምድር ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ ሰጥቶአችኋል ፤ መሣሪያችሁን ፡ ይዛችሁ ፡ እናንተ ፡ አርበኞች ፡ ሁሉ ፡ በወንድሞቻችሁ ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ትሻገራላችሁ ። ፲፱ ነገር ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ከብቶች ፡ እንዳሉአችሁ ፡ አውቃለሁና ፡ ሴቶቻችሁና ፡ ልጆቻችሁ ፡ ከብቶቻችሁም ፡ በሰጠኋችሁ ፡ ከተሞች ፡ ይቀመጣሉ ፤ ፳ ይኸውም ፡ እግዚአብሔር ፡ እናንተን ፡ እንዳሳረፈ ፥ ወንድሞቻችሁን ፡ እስኪያሳርፍ ፡ ድረስ ፥ እነርሱም ፡ ደግሞ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚሰጣቸውን ፡ ምድር ፡ እስኪወርሱ ፡ ድረስ ፡ ነው ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እናንተ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ሰጠኋችሁ ፡ ርስት ፡ ትመለሳላችሁ ። ፳፩ በዚያም ፡ ጊዜ ፡ ኢያሱን ፡— አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእነዚህ ፡ በሁለቱ ፡ ነገሥት ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፡ ዓይኖችህ ፡ አይተዋል ፤ እንዲሁ ፡ በምታልፍበቸው ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያደርጋል ። ፳፪ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ እርሱ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ይዋጋልና ፡ አትፈሩቸውም ፡ ብዬ ፡ አዘዝሁት ።

፳፫ በዚያም ፡ ዘመን ፡ እኔ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፳፬ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ ለመንሁ ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ ታላቅነትህን ፡ የጸናችውንም ፡ እጅህን ፡ ለእኔ ፡ ለባሪያህ ፡ ማሳየት ፡ ጀምረሃል ፤ በሰማይና ፡ በምድርም ፡ እንደ ፡ ሥራህ ፡ እንደ ፡ ኃይልህም ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ የሚችል ፡ አምላክ ፡ ማን ፡ ነው ? ፳፭ እኔ ፡ ልሻገር ፥ በዮርዳኖስም ፡ ማዶ ፡ ያለችውን ፡ መልካሚቱን ፡ ምድር ፡ ያንም ፡ መልካሙን ፡ ተራራማውን ፡ አገር ፡ ሊባኖስንም ፡ ልይ ። ፳፮ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በእናንተ ፡ ምክንያት ፡ ተቈጣኝ ፡ አልሰማኝምም ፤ እግዚአብሔርም ፡ አለኝ ፡— ይበቃሃል ፤ በዚህ ፡ ነገር ፡ ደግመህ ፡ አትናገረኝ ። ፳፯ ይህን ፡ ዮርዳኖስን ፡ አትሻገርምና ፡ ወደ ፡ ፈስጋ ፡ ራስ ፡ ውጣ ፤ ዓይንህንም ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ወደ ፡ ሰሜንም ፡ ወደ ፡ ደቡብም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅም ፡ አንሥተህ ፡ በዓይንህ ፡ ተመልከት ። ፳፰ ኢያሱ ፡ በዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ፊት ፡ ይሻገራልና ፥ አንተም ፡ የምታያትን ፡ ምድር ፡ እርሱ ፡ ያወርሳቸዋልና ፡ ኢያሱን ፡ እዘዘው ፥ አደፋፍረውም ፥ አጽናውም ። ፳፱ በቤተ ፡ ፌጎርም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በሸለቆው ፡ ውስጥ ፡ ተቀመጥን ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ አሁንም ÷ እስራኤል ፡ ሆይ ÷ እንድታደርጉ
አቸው ፡ በሕይወትም ፡ እንድትኖሩ ÷ የአባቶቻ
ችሁም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደሚሰጣ
ችሁ ፡ ምድር ፡ ገብታችሁ ፡ እንድትወርሱ ÷ የማ
ስተምራችሁን ፡ ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ ስሙ ።
፪ እኔ ፡ ያዘዝኋችሁን ፡ የአምላካችሁን ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ትጠብቃላችሁ ፡ እንጂ ፡
በዘዝኋችሁ ፡ ቃል ፡ ላይ ፡ አትጨምሩም ÷ ከእ
፫ ርሱም ፡ አታጐድሉም ። ብዔልፌጎርን ፡ የተ
ከተሉትን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ከመካከላችሁ ፡ እንዳጠፋ ÷ እግዚአብ
ሔር ፡ በብዔልፌጎር ፡ ያደረገውን ፡ ዓይኖቻችሁ ፡
፬ አይተዋል ። እናንተ ፡ ግን ፡ አምላካችሁን ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ የተከተላችሁ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡
፭ ሁላችሁ ፡ በሕይወት ፡ ትኖራላችሁ ። እነሆ ÷
እናንተ ፡ ገብታችሁ ፡ በምትወርሱአት ፡ ምድር ፡
ውስጥ ፡ እንዲህ ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አምላኬ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘኝ ፡ ሥርዓትንና ፡ ፍር
፮ ድን ፡ አስተማርኋችሁ ። ጠብቁአት ፡ አድርጉአ
ትም ፤ ይህችን ፡ ሥርዓት ፡ ሁሉ ፡ ሰምተው ፡—
በእውነት ፡ ይህ ፡ ታላቅ ፡ ሕዝብ ፡ ጠቢብና ፡ አስ
ተዋይ ፡ ሕዝብ ፡ ነው ፡ በሚሉ ፡ በአሕዛብ ፡ ፊት ፡
ጥበባችሁና ፡ ማስተዋላችሁ ፡ ይህ ፡ ነውና ፤
፯ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ በምንጠራው ፡
ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ እንደሚቀርበን ÷ አምላኩ ፡ ወደ ፡
እርሱ ፡ የቀረበው ፡ ታላቅ ፡ ሕዝብ ፡ ማን ፡ ነው ?
፰ በዓይናችሁ ፡ ፊት ፡ ዛሬ ፡ እንደማኖራት ፡ እን
ደዚህች ፡ ሕግ ፡ ሁሉ ፡ ጽድቅ ፡ የሆነች ፡ ሥርዓ
ትና ፡ ፍርድ ፡ ያለው ፡ ታላቅ ፡ ሕዝብ ፡ ማን ፡
ነው ?

፱ ፲ እግዚአብሔር ፡— ሕዝቡን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ሰብ
ስብ ÷ በምድርም ፡ በሕይወት ፡ በሚኖሩበት ፡
ዘመን ፡ ሁሉ ፡ እኔን ፡ መፍራት ፡ ይማሩ ፡ ዘንድ ÷
ልጆቻቸውንም ፡ ያስተምሩ ፡ ዘንድ ፡ ቃሌን ፡
አሰማቸዋለሁ ፡ ብሎ ፡ በተናገረኝ ፡ ጊዜ ÷ በአ
ምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በኮሬብ ፡ በቆ
ምህበት ፡ ቀን ፡ ዓይኖችህ ፡ ያዩትን ፡ ነገር ፡ እን
ዳትረሳ ÷ በሕይወትህም ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ከል
ብህ ፡ እንዳይወድቅ ፡ ተጠንቀቅ ÷ ነፍስህንም ፡
በትጋት ፡ ጠብቅ ፤ ለልጆችህም ፡ ለልጅ ፡ ልጆች
፲፩ ህም ፡ አስታውቀው ። እናንተም ፡ ቀርባችሁ ፡
ከተራራው ፡ በታች ፡ ቆማችሁ ፡ ነበር ፤ እስከ ፡
ሰማይም ፡ መከከል ፡ ድረስ ፡ እሳት ፡ በተራራው ፡
ላይ ፡ ይነድድ ፡ ነበር ፤ ጨለማና ፡ ደመና ፡ ድቅ
፲፪ ድቅ ፡ ጨለማም ፡ ነበረ ። እግዚአብሔርም ፡
በእሳት ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ ተናገራችሁ ፤ የቃልን ፡
ድምፅ ፡ ሰማችሁ ÷ መልክ ፡ ግን ፡ አላያችሁም ፤
፲፫ ድምፅን ፡ ብቻ ፡ ሰማችሁ ። ታደርጉትም ፡
ዘንድ ፡ ያዘዛችሁን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አሥሩን ፡
ቃላት ፡ ነገራችሁ ፤ በሁለቱም ፡ በድንጋይ ፡ ጽላ
፲፬ ቶች ፡ ላይ ፡ ጻፋቸው ። ትወርሱአት ፡ ዘንድ ፡
ተሻግራችሁ ፡ በምትገቡባት ፡ ምድር ፡ የምታ
ደርጉአትን ፡ ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ አስተምራችሁ ፡
ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አዘዘኝ ።

፲፭ እግዚአብሔር ፡ በኮሬብ ፡ በእሳት ፡ ውስጥ ፡
ሆኖ ፡ በተናገራችሁ ፡ ጊዜ ፡ መልክ ፡ ከቶ ፡ አላ
፲፮ ያችሁምና ፡ እጅግ ፡ ተጠንቀቁ ፤ እንዳትረክሱ ÷
የተቀረጸውን ፡ ምስል ፡ የማናቸውንም ፡ ነገር ፡
ምሳሌ ÷ በወንድ ፡ ወይም ፡ በሴት ፡ መልክ ፡ የተ
፲፯ ሠራውን ÷ በምድር ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ የእንስሳን ፡
ሁሉ ፡ ምሳሌ ÷ በሰማይም ፡ በታች ፡ የሚበረረ
፲፰ ውን ፡ የወፍን ፡ ሁሉ ፡ ምሳሌ ÷ በምድርም ፡
ላይ ፡ የሚሽከረከረውን ፡ ሁሉ ፡ ምሳሌ ÷ ከምድ
ርም ፡ በታች ፡ በውኃ ፡ ውስጥ ፡ የሚኖረውን ፡
፲፱ የዓሣን ፡ ሁሉ ፡ ምሳሌ ፡ እንዳታደርጉ ÷ ዓይኖ
ችህን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አንሥተህ ፡ አምላክህ ፡
እግዚአብሔር ፡ ከሰማይ ፡ ሁሉ ፡ በታች ፡ ላሉት ፡
አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ የሰጣቸውን ፡ ፀሐይንና ፡ ጨረ
ቃን ፡ ከዋክብትንና ፡ የሰማይን ፡ ሠራዊት ፡
ሁሉ ፡ በየህ ፡ ጊዜ ÷ ሰግደህላቸው ፡ አምልካቸ
፳ ቸውም ፡ እንዳትስት ፡ ተጠንቀቅ ። እናንተን ፡
ግን ፡ እንደ ፡ ዛሬው ፡ ሁሉ ፡ የርስቱ ፡ ሕዝብ ፡
ትሆኑለት ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወስዶ ፡ ከብ
፳፩ ረት ፡ እቶን ፡ ከግብፅ ፡ አወጣችሁ ። እግዚአብ
ሔርም ፡ በእናንተ ፡ ምክንያት ፡ ተቈጣኝ ÷ ዮር
ዳኖስንም ፡ እንዳልሻገር ÷ አምላክህም ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ ወደሚሰጥህ ፡ ወደ ፡
፳፪ መልካሚቱ ፡ ምድር ፡ እንዳልገባ ፡ ማለ ። እኔ ፡
ግን ፡ በዚህች ፡ ምድር ፡ እሞታለሁ ÷ ዮርዳኖስ
ንም ፡ አልሻገርም ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ትሻገራላ
ችሁ ÷ ያችንም ፡ መልካሚቱን ፡ ምድር ፡ ትወ
፳፫ ርሳላችሁ ። አምላካችሁም ፡ እግዚአብሔር ፡
ከእናንተ ፡ ጋር ፡ የተማማለውን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
እንዳትረሱ ÷ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ የከ
ለከለውን ፡ በማናቸውም ፡ ቅርጽ ፡ የተቀረጸ
ውን ፡ ምስል ፡ እንዳታደርጉ ፡ ተጠንቀቁ ።
፳፬ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚበላ ፡ እሳት ፡
ቀናተኛም ፡ አምላክ ፡ ነውና ።

፳፭ ልጆችን ፡ የልጅ ፡ ልጆችንም ፡ በወለዳችሁ ፡
ጊዜ ÷ በምድሪቱም ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ በተቀመጣ
ችሁ ፡ ጊዜ ÷ በረከሳችሁም ፡ ጊዜ ÷ በማናቸ
ውም ፡ ቅርጽ ፡ የተቀረጸውን ፡ ምስል ፡ በደረጋ
ችሁ ፡ ጊዜ ÷ ታስቈጡትም ፡ ዘንድ ፡ በአምላክ
ችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ የሆነውን ፡
፳፮ ነገር ፡ በሠራችሁ ፡ ጊዜ ÷ ትወርሱአት ፡ ዘንድ ፡
ዮርዳኖስን ፡ ተሻግራችሁ ፡ ከምትገቡባት ፡
ምድር ፡ ፈጥናችሁ ፡ እንድትጠፉ ፡ እኔ ፡ ዛሬ ፡
ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ በእናንተ ፡ አስመሰክራ
ለሁ ፤ ፈጽሞም ፡ ትጠፋላችሁ ፡ እንጂ ፡ ረጅም ፡
፳፯ ዘመን ፡ አትቀመጡበትም ። እግዚአብሔርም ፡
በአሕዛብ ፡ መከከል ፡ ይበትናችኋል ÷ እግዚአ
ብሔር ፡ በውስጣቸው ፡ በሚያኖራችሁ ፡ በአሕ
ዛብ ፡ መከከልም ፡ ጥቂቶች ፡ ሆናችሁ ፡ ትቀራ
፳፰ ላችሁ ። በዚያም ፡ የማያዩትን ፡ የማይሰሙት
ንም ፡ የማይበሉትንም ፡ የማያሸቱትንም ÷ በሰው ፡
እጅ ፡ ከእንጨትና ፡ ከድንጋይ ፡ የተሠሩትን ፡ አማ

ልክት ፡ ታመልካላችሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ ከዚያ ፡ [፳፱] አምላካችሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትሻላችሁ ፤ በልብህም ፡ ሁሉ ፡ በነፍስህም ፡ ሁሉ ፡ የፈለግኸው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ታገኘዋለህ ። [፴] ይህም ፡ ሁሉ ፡ በደረሰብህ ፡ ጊዜ ፥ ስትጨነቅ ፥ በዘመኑ ፡ ፍጻሜ ፡ ወደ ፡ አምላክህ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትመለሳለህ ፥ ቃሉንም ፡ ትሰማለህ ። [፴፩] አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ መሐሪ ፡ አምላክ ፡ ነውና ፡ አይተውህም ፥ አያጠፋህምም ፥ ለአባቶችህም ፡ የማለላቸውን ፡ ቃል ፡ ኪዳኑን ፡ አይረሳም ።

[፴፪] እግዚአብሔር ፡ ሰውን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ከፈጠረው ፡ ጀምሮ ፥ ከሰማይ ፡ ዳር ፡ እስከ ፡ ዳርቻዋ ፡ ድረስ ፡ ከቶ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡ ወይም ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ያለ ፡ ተሰምቶ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከአንተ ፡ በፊት ፡ የነበረውን ፡ የቀደመውን ፡ ዘመን ፡ ጠይቅ ። [፴፫] አንተ ፡ ከእሳት ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ ሲናገር ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ድምፅ ፡ እንደ ፡ ሰማህ ፥ ሌላ ፡ ሕዝብ ፡ ሰምቶ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራልን ? [፴፬] አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዓይናችሁ ፡ ፊት ፡ በግብፅ ፡ ለእናንተ ፡ እንደ ፡ ሠራው ፡ ሁሉ ፥ በፈተናና ፡ በተአምራት ፥ በድንቅና ፡ በሰልፍ ፥ በጸናች ፡ እጅና ፡ በተዘረጋ ፡ ክንድ ፡ በታላቅም ፡ ማስፈራት ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሌላ ፡ ሕዝብ ፡ መካከል ፡ ገብቶ ፡ ለእርሱ ፡ ሕዝብን ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ፡ ሞክሮ ፡ ነበርን ? [፴፭] እግዚአብሔርም ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ለአንተ ፡ ተገለጠ ፤ ከእርሱም ፡ ሌላ ፡ አምላክ ፡ የለም ። [፴፮] ያስተምርህ ፡ ዘንድ ፡ ከሰማይ ፡ ድምፁን ፡ አሰማህ ፤ በምድርም ፡ ላይ ፡ ታላቁን ፡ እሳት ፡ አሳየህ ፤ ከእሳትም ፡ ውስጥ ፡ ቃሉን ፡ ሰማህ ። [፴፯፡፴፰] አባቶችህን ፡ ወድዶአልና ፡ ከእነርሱ ፡ በኋላ ፡ ዘራቸውን ፡ መረጠ ፥ ዛሬ ፡ እንደ ፡ ሆነው ፡ ሁሉ ፡ ከአንተ ፡ የጸኑትን ፡ ታላላቆችን ፡ አሕዛብ ፡ በፊትህ ፡ እንዲያወጣ ፥ አንተንም ፡ እንዲያገባህ ፥ ምድራቸውንም ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ እንዲሰጥህ ፥ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ሆኖ ፡ በታላቅ ፡ ኃይሉ ፡ ከግብፅ ፡ አወጣህ ። [፴፱] እንግዲህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በላይ ፡ በሰማይ ፡ በታችም ፡ በምድር ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ሌላም ፡ እንደሌለ ፡ ዛሬ ፡ እወቅ ፥ በልብህም ፡ ያዝ ። [፵] ለአንተ ፡ ከአንተም ፡ በኋላ ፡ ለልጆችህ ፡ መልካም ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፥ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ በሚሰጥህ ፡ ምድር ፡ ዕድሜህ ፡ ይረዝም ፡ ዘንድ ፥ እኔ ፡ ዛሬ ፡ የማዝዝህን ፡ ሥርዓቱንና ፡ ትእዛዙን ፡ ጠብቅ ።

[፵፩፡፵፪] በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሙሴ ፡ ትናንት ፡ ከትናንት ፡ በስቲያም ፡ ጠላቱ ፡ ያልሆነውን ፡ ባልንጀራውን ፡ ሳያውቅ ፡ የገደለ ፡ ገዳዩ ፡ ይሸሽባቸው ፡ ዘንድ ፥ ከእነዚህም ፡ ከተሞች ፡ ወደ ፡ አንዲቱ ፡ ሸሽቶ ፡ በሕይወት ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ሦስት ፡ ከተሞች ፡ ለየ ። [፵፫] ከተሞቹም ፡ ለሮቤል ፡ ነገድ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ በደልዳላ ፡ ስፍራ ፡ ያለ ፡ ቦሶር ፥ ለጋድም ፡ ነገድ ፡ በገለዓድ ፡ ያለ ፡ ራሞት ፥ ለምናሴም ፡ ነገድ ፡ በባሳን ፡ ያለ ፡ ጎላን ፡ ነበሩ ።

[፵፬] ሙሴም ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ያኖራት ፡ ሕግ ፡ ይህች ፡ ናት ፤ [፵፭፡፵፮] ሙሴና ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከግብፅ ፡ ከወጡ ፡ በኋላ ፡ በመቱት ፥ በሐሴቦን ፡ ተቀምጦ ፡ በነበረው ፡ በአሞራውያን ፡ ንጉሥ ፡ በሴዎን ፡ ምድር ፥ በቤተ ፡ ፌጎር ፡ አንጻር ፡ ባለው ፡ ሸለቆ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፥ ከግብፅ ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፡ ሙሴ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የተናገረው ፡ ምስክርና ፡ ሥርዓት ፡ ፍርድም ፡ ይህ ፡ ነው ። [፵፯] የእርሱንና ፡ የባሳንን ፡ ንጉሥ ፡ የዐግን ፡ ምድር ፥ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ የነበሩትን ፡ የሁለቱን ፡ የአሞራውያንን ፡ ነገሥታት ፡ ምድር ፥ [፵፰] በአርኖን ፡ ወንዝ ፡ ዳር ፡ካለችው ፡ ከአሮዔር ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሲዎን ፡ ተራራ ፡ እስከ ፡ አርሞንዔም ፡ ድረስ ፥ [፵፱] በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ከፈስጋ ፡ ተራራ ፡ በታች ፡ ያለውን ፡ ዓረባ ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ዓረባ ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፡ ወሰዱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

[፩] ሙሴም ፡ እስራኤልን ፡ ሁሉ ፡ ጠርቶ ፡ አላቸው ፦ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ እንድትማሩአት ፡ በማድረግም ፡ እንድትጠብቁአት ፡ ዛሬ ፡ በጆሮአችሁ ፡ የምናገራትን ፡ ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ ስሙ ። [፪] አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ በኮሬብ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረገ ። [፫] እግዚአብሔር ፡ ዛሬ ፡ በዚህ ፡ በሕይወት ፡ ካለነው ፡ ከእኛ ፡ ከሁላችን ፡ ጋር ፡ እንጂ ፡ ከአባቶቻችን ፡ ጋር ፡ ይህችን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አላደረገም ። [፬] በተራራው ፡ ላይ ፡ በእሳት ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ተናገራችሁ ። [፭] እኔ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ እነግራችሁ ፡ ዘንድ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡ ቆሜ ፡ ነበር ፤ እናንተ ፡ በእሳቱ ፡ ምክንያት ፡ ፈርታችኋልና ፥ ወደ ፡ ተራራውም ፡ አልወጣችሁምና ። እርሱም ፡ አለ ፦

[፮] ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ከባርነት ፡ ቤት ፡ ያወጣሁህ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ እኔ ፡ ነኝ ።

[፯] ከእኔ ፡ በቀር ፡ ሌሎች ፡ አማልክት ፡ አይሁኑልህ ።

[፰] በላይ ፡ በሰማይ ፡ ካለው ፥ በታችም ፡ በምድር ፡ ካለው ፥ ከምድርም ፡ በታች ፡ በውኃ ፡ ካለው ፡ ነገር ፡ የማናቸውንም ፡ ምሳሌ ፡ የተቀረጸውንም ፡ ምስል ፡ ለአንተ ፡ አታድርግ ፤ [፱፡፲] በሚጠሉኝ ፡ እስከ ፡ ሦስተኛና ፡ እስከ ፡ አራተኛ ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ የአባቶችን ፡ ኃጢአት ፡ በልጆች ፡ ላይ ፡ የማመጣ ፤ ለሚወድዱኝ ፡ ትእዛዜንም ፡ ለሚጠብቁ ፡ እስከ ፡ ሺህ ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ ምሕረትን ፡ የማደርግ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ ቀናተኛ ፡ አምላክ ፡ ነኝና ፡ አትስገድላቸው ፥ አታምልካቸውም ።

[፲፩] የእግዚአብሔርን ፡ የአምላክህን ፡ ስም ፡ በከንቱ ፡ አትጥራ ፤ እግዚአብሔር ፡ ስሙን ፡ በከንቱ ፡ የሚጠራውን ፡ ከበደል ፡ አያነጻውምና ።

፲፪፤ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ እንዳዘዘህ ፡ የሰን
፲፫፤ በትን ፡ ቀን ፡ ትቀድሰው ፡ ዘንድ ፡ ጠብቅ ። ስድ
ስት ፡ ቀን ፡ ሥራ ፡ ተግባርህንም ፡ ሁሉ ፡ አድ
፲፬፤ ርግ ፥ ሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ግን ፡ ለእግዚአብሔር ፡
አምላክህ ፡ ሰንበት ፡ ነው ፤ አንተ ፡ እንደምታ
ርፍ ፡ ሎሌህና ፡ ገረድህ ፡ ያርፉ ፡ ዘንድ ፥ አንተ ፡
ወንድ ፡ ልጅህም ፡ ሴት ፡ ልጅህም ፡ ሎሌህም ፡
ገረድህም ፡ በሬህም ፡ አህያህም ፡ ከብትህም ፡
ሁሉ ፡ በደጆችህም ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ እንግዳ ፡
፲፭፤ በእርሱ ፡ ምንም ፡ ሥራ ፡ አትሥሩ ። አንተም ፡
በግብፅ ፡ ባሪያ ፡ እንደ ፡ ነበርህ ፡ አስብ ፤ እግዚአ
ብሔር ፡ አምላክህ ፡ በጸናች ፡ እጅና ፡ በተዘረጋ ፡
ክንድ ፡ ከዚያ ፡ አወጣህ ፤ ስለዚህ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ አምላክህ ፡ የሰንበትን ፡ ቀን ፡ ትጠብቅ ፡
፲፮፤ ዘንድ ፡ አዘዘህ ። እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡
እንዳዘዘህ ፡ አባትህንና ፡ እናትህን ፡ አክብር ፤
እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ በሚሰጥህ ፡ ምድር ፡
ላይ ፡ ዕድሜህ ፡ እንዲረዝም ፥ መልካምም ፡ እን
ዲሆንልህ ።
፲፯፤ አትግደል ።
፲፰፤ አታመንዝር ።
፲፱፤ አትስረቅ ።
፳፤ በባልንጀራህ ፡ ላይ ፡ በሐሰት ፡ አትመስክር ።
፳፩፤ የባልንጀራህን ፡ ሚስት ፡ አትመኝ ፤ የባልን
ጀራህንም ፡ ቤት ፡ እርሻውንም ፡ ሎሌውንም ፡
ገረዱንም ፡ በሬውንም ፡ አህያውንም ፥ ከባልን
ጀራህ ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉ ፡ ማናቸውንም ፡ አት
መኝ ።
፳፪፤ እግዚአብሔር ፡ በተራራው ፡ ላይ ፡ በእሳትና ፡
በደመናው ፡ በጨለማውም ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ በታ
ላቅ ፡ ድምፅ ፡ እነዚህን ፡ ቃሎች ፡ ለጉባኤአችሁ ፡
ሁሉ ፡ ተናገረ ፤ ምንም ፡ ምን ፡ አልጨመረም ።
በሁለቱም ፡ የድንጋይ ፡ ጽላቶች ፡ ላይ ፡ ጻፋቸው ፥
፳፫፤ ለእኔም ፡ ሰጣቸው ። ተራራው ፡ በእሳት ፡ ሲነ
ድድ ፡ ከጨለማው ፡ ውስጥ ፡ ድምፁን ፡ በሰማ
ችሁ ፡ ጊዜ ፥ እናንተ ፥ የነገዶቻችሁ ፡ አለቆች ፡
፳፬፤ ሽማግሌዎቻችሁም ፥ ወደ ፡ እኔ ፡ ቀረባችሁ ፤ አላ
ችሁም ፡— እነሆ ፥ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡
ክብሩንና ፡ ታላቅነቱን ፡ አሳይቶናል ፥ ከእሳ
ቱም ፡ ውስጥ ፡ ድምፁን ፡ ሰምተናል ፤ እግዚ
አብሔርም ፡ ከሰው ፡ ጋር ፡ ሲነጋገር ፡ ሰውዮ
ውም ፡ በሕይወት ፡ ሲኖር ፡ ዛሬ ፡ አይተናል ።
፳፭፤ አሁን ፡ እንግዲህ ፡ ይህች ፡ ታላቂቱ ፡ እሳት ፡
ታቃጥለናለችና ፡ ለምን ፡ እንሞታለን ? እኛ ፡
የአምላካችንን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ድምፅ ፡
፳፮፤ ደግሞ ፡ ብንሰማ ፡ እንሞታለን ። ከሥጋ ፡ ለባሽ ፡
ሁሉ ፡ እኛ ፡ እንደ ፡ ሰማን ፡ በእሳት ፡ ውስጥ ፡
ሆኖ ፡ ሲናገር ፡ የሕያው ፡ አምላክን ፡ ድምፅ ፡
፳፯፤ ሰምቶ ፡ በሕይወቱ ፡ የኖረ ፡ ማን ፡ ነው ? አንተ ፡
ቅረብ ፥ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚለ
ውን ፡ ሁሉ ፡ ስማ ፤ አምላካችን ፡ እግዚአብሔ
ርም ፡ ለአንተ ፡ የሚናገረውን ፡ ሁሉ ፡ ለእኛ ፡
ንገረን ፤ እኛም ፡ ሰምተን ፡ እናደርገዋለን ።
፳፰፤ በተናገራችሁኝም ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡
የእናንተን ፡ ቃል ፡ ድምፅ ፡ ሰማ ፤ እግዚአብሔ
ርም ፡ አለኝ ፡— ይህ ፡ ሕዝብ ፡ የተናገሩህን ፡
ቃል ፡ ድምፅ ፡ ሰምቼአለሁ ፤ የተናገሩህ ፡ ሁሉ ፡
፳፱፤ መልካም ፡ ነገር ፡ ነው ። ለእነርሱ ፡ ለዘላለምም ፡
ለልጆቻቸው ፡ መልካም ፡ ይሆንላቸው ፡ ዘንድ ፥
እንዲፈሩኝ ፡ ሁልጊዜም ፡ ትእዛዜን ፡ ሁሉ ፡ እን
ዲጠብቁ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ልብ ፡ ምነው ፡ በሆነ
፴፤ ላቸው ! ሂደህ ፡— ወደ ፡ ድንኳናችሁ ፡ ተመ
፴፩፤ ለሱ ፡ በላቸው ። አንተ ፡ ግን ፡ በዚህ ፡ በእኔ ፡
ዘንድ ፡ ቁም ፥ ርስት ፡ አድርጌ ፡ በምሰጣቸውም ፡
ምድር ፡ ላይ ፡ ያደርጉአት ፡ ዘንድ ፡ የምታስተ
ምራቸውን ፡ ትእዛዜንና ፡ ሥርዓቴን ፡ ፍርዴ
፴፪፤ ንም ፡ ሁሉ ፡ እነግርሃለሁ ። እግዚአብሔር ፡
አምላካችሁ ፡ እንዳዘዛችሁ ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡
ጠብቁ ፤ ከእርሱም ፡ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡
፴፫፤ ፈቀቅ ፡ አትበሉ ። በሕይወት ፡ እንድትኖሩ ፥
መልካምም ፡ እንዲሆንላችሁ ፥ በምትወርሱአ
ትም ፡ ምድር ፡ ዕድሜአችሁ ፡ እንዲረዝም ፥
እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ በዘዛችሁ ፡ መን
ገድ ፡ ሁሉ ፡ ሂዱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩፤፪፤ አንተ ፡ ልጅህም ፡ የልጅ ፡ ልጅህም ፡ በዕድ
ሜአችሁ ፡ ሁሉ ፡ ልትወርሱአት ፡ በምትገቡ
ባት ፡ ምድር ፡ ታደርጉአት ፡ ዘንድ ፥ አምላክ
ህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈርተህ ፡ እኔ ፡ ለአንተ ፡
ያዘዝሁትን ፡ ሥርዓቱንና ፡ ትእዛዙን ፡ ሁሉ ፡
ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፥ ዕድሜህም ፡ ይረዝም ፡ ዘንድ ፥
አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳስተምራ
ችሁ ፡ ያዘዛት ፡ ትእዛዝና ፡ ሥርዓት ፡ ፍርድም ፡
፫፤ ይህች ፡ ናት ። እንግዲህ ፥ እስራኤል ፡ ሆይ ፥
ስማ ፤ መልካምም ፡ እንዲሆንልህ ፥ የአባቶች
ህም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡
ወተትና ፡ ማር ፡ በምታፈስሰው ፡ ምድር ፡ እጅግ ፡
እንድትበዛ ፥ ታደርጋት ፡ ዘንድ ፡ ጠብቅ ።
፬፤ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ ስማ ፤ አምላካችን ፡ እግ
፭፤ ዚአብሔር ፡ አንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ፤ አን
ተም ፡ አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ በፍጹም ፡
ልብህ ፡ በፍጹምም ፡ ነፍስህ ፡ በፍጹምም ፡ ኃይ
፮፤ ልህ ፡ ውደድ ። እኔም ፡ ዛሬ ፡ አንተን ፡ የማዝ
፯፤ ዘውን ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ በልብህ ፡ ያዝ ። ለልጆ
ችህም ፡ አስተምረው ፥ በቤትህም ፡ ስትቀመጥ ፥
በመንገድም ፡ ስትሄድ ፥ ስትተኛም ፥ ስትነሣም ፡
፰፤ ተጫወተው ። በእጅህም ፡ ምልክት ፡ አድር
ገህ ፡ እሰረው ፤ በዓይኖችህም ፡ መካከል ፡ እንደ ፡
፱፤ ክታብ ፡ ይሁንልህ ። በቤትህም ፡ መቃኖች ፡
በደጃፍህም ፡ በሮች ፡ ላይ ፡ ጻፈው ።
፲፤ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአንተ ፡ ሊሰጣት ፡
ለአባቶችህ ፡ ለአብርሃምና ፡ ለይስሐቅ ፡ ለያዕ
ቆብም ፡ ወደ ፡ ማለላቸው ፡ ምድር ፡ ባገባህ ፡
ጊዜ ፤ ያልሠራሃቸውንም ፡ ታላቅና ፡ መልካም ፡
፲፩፤ ከተሞች ፥ ያልሞላሃቸውንም ፡ ሀብትን ፡ የሞሉ ፡
ቤቶች ፥ ያልማስሃቸውንም ፡ የተማሱ ፡ ጕድጓ
ዶች ፥ ያልተከልሃቸውንም ፡ ወይንና ፡ ወይራ ፡

በሰጠህ ፡ ጊዜ ÷ በበላህና ፡ በጠገብህም ፡ ጊዜ ፤
፲፪ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ከባርነት ፡
ቤት ፡ ያወጣህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዳትረሳ ፡
፲፫ ፡ ተጠንቀቅ ። አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡
ፍራ ፤ እርሱንም ፡ አምልክ ፤ በስሙም ፡ ማል ።
፲፬ ፡ ፲፭ ፡ በመካከልህ ፡ ያለው ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡
ቀናተኛ ፡ አምላክ ፡ ነውና ፡ የአምላክህ ፡ የእግ
ዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ እንዳይነድድብህ ፡ ከምድ
ርም ፡ ፊት ፡ እንዳያጠፋህ ÷ በዙሪያችሁ ፡ ያሉት ፡
አሕዛብ ፡ የሚያመልኩአቸውን ፡ ሌሎችን ፡ አማ
ልክት ፡ አትከተሉ ።
፲፮ ፡ በማሳህ ፡ እንደ ፡ ፈተናችሁት ፡ አምላካች
፲፯ ፡ ሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አትፈታተኑት ። ለእ
ናንተ ፡ ያዘዘውን ፡ የአምላካችሁን ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ምስክሩንም ፡ ሥርዓቱንም ፡
፲፰ ፡ ፲፱ ፡ አጥብቃችሁ ፡ ጠብቁ ። መልካምም ፡ ይሆን
ልህ ፡ ዘንድ ÷ እግዚአብሔርም ፡ ለአባቶችህ ፡
ወደ ፡ ማለላቸው ፡ ወደ ፡ መልካሚቱ ፡ ምድር ፡
ገብተህ ፡ እርስዋን ፡ ትወርስ ፡ ዘንድ ÷ እግዚአ
ብሔርም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ጠላቶችህን ፡ ሁሉ ፡
ከፊትህ ፡ ያወጣልህ ፡ ዘንድ ÷ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ቅኑንና ፡ መልካሙን ፡ አድርግ ።
፳ ፡ በኋለኛው ፡ ዘመንም ፡ ልጅህ ፡ — አምላካችን ፡
እግዚአብሔር ፡ ያዘዛችሁ ፡ ምስክርና ፡ ሥርዓት ፡
ፍርድስ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብሎ ፡ በጠየቀህ ፡
፳፩ ፡ ጊዜ ÷ አንተ ፡ ልጅህን ፡ በለው ፡ — በግብፅ ፡ የፈ
ርዖን ፡ ባሪያዎች ፡ ነበርን ፤ እግዚአብሔርም ፡
፳፪ ፡ በጽኑ ፡ እጅ ፡ ከግብፅ ፡ አወጣን ፤ እግዚአብሔ
ርም ፡ በግብፅና ፡ በፈርዖን ፡ በቤቱም ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ እኛ ፡ እያየን ፡ ታላቅና ፡ ክፉ ፡ ምልክት ፡ ተአ
፳፫ ፡ ምራትም ፡ አደረገ ። ለአባቶቻችን ፡ ወደ ፡ ማለ
ላቸው ፡ ምድር ፡ አግብቶ ፡ እርስዋን ፡ ይሰጠን ፡
፳፬ ፡ ዘንድ ፡ ከዚያ ፡ አወጣን ። እንደ ፡ ዛሬም ፡ በሕ
ይወት ፡ እንዲያኖረን ÷ ሁልጊዜም ፡ መልካም ፡
እንዲሆንልን ÷ አምላካችንን ፡ እግዚአብሔርን ፡
እንፈራ ፡ ዘንድ ÷ ይህችንም ፡ ሥርዓት ፡ ሁሉ ፡
እናደርግ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ አዘዘን ።
፳፭ ፡ እርሱም ፡ እንዳዘዘን ፡ በአምላካችን ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ፊት ፡ እናደርጋት ፡ ዘንድ ፡ ይህችን ፡
ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ብንጠብቅ ፡ ለእኛ ፡ ጽድቅ ፡
ይሆንልናል ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልትወርሳት ፡
ወደምትገባበት ፡ ምድር ፡ባመጣህ ፡ ጊዜ ÷ ከፊት
ህም ፡ ብዙ ፡ አሕዛብን ÷ ከአንተ ፡ የበለጡትን ፡
የበረቱትንም ፡ ሰባቱን ፡ አሕዛብ ÷ ኬጢያዊውን ፡
ጌርጌሳዊውንም ፡ አሞራዊውንም ፡ ከነዓናዊው
ንም ፡ ፌርዛዊውንም ፡ ኤዊያዊውንም ፡ ኢያቡ
፪ ፡ ሳዊውንም ፡ ባወጣ ፡ ጊዜ ÷ አምላክህ ፡ እግዚአ
ብሔርም ፡ በእጅህ ፡ አሳልፎ ፡ በሰጣቸው ፡ በመ
ታሃቸውም ፡ ጊዜ ÷ ፈጽመህ ፡ አጥፋቸው ፤ ከእ
ነርሱም ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አታድርግ ÷ አት
፫ ፡ ማራቸውም ፤ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ አትጋባ ፤
ሴት ፡ ልጅህን ፡ ለወንድ ፡ ልጁ ፡ አትስጥ ÷ ሴት ፡
፬ ፡ ልጁንም ፡ ለወንድ ፡ ልጅህ ፡ አትውሰድ ። እን
ዳይከተለኝ ፡ ሌሎችንም ፡ አማልክት ፡ እንዲያ
መልክ ፡ ልጅህን ፡ ያስታልና ፤ የእግዚአብሔ
ርም ፡ ቍጣ ፡ ይነድድባችኋል ÷ ፈጥኖም ፡ ያጠ
፭ ፡ ፋችኋል ። ነገር ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አድርጉባቸው ፤
መሠዊያቸውን ፡ አፍርሱ ÷ ሐውልቶቻቸው
ንም ፡ ሰባብሩ ÷ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶቻቸውንም ፡
ቍረጡ ÷ የተቀረጸውን ፡ ምስላቸውንም ፡ በእ
ሳት ፡ አቃጥሉ ።
፮ ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አንተ ፡ ቅዱስ ፡
ሕዝብ ፡ ነህና ፤ በምድር ፡ ፊት ፡ ከሚኖሩ ፡ አሕዛብ ፡
ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ለእርሱ ፡ ለራሱ ፡ ሕዝብ ፡ ትሆን
ለት ፡ ዘንድ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ መረ
፯ ፡ ጠህ ። እግዚአብሔርም ፡ የወደዳችሁና ፡ የመ
ረጣችሁ ፡ ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ በቍጥር ፡ ስለ ፡ በዛ
ችሁ ፡ አይደለም ፤ እናንተ ፡ ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡
፰ ፡ በቍጥር ፡ ጥቂቶች ፡ ነበራችሁና ፤ ነገር ፡ ግን ፡
እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ወደዳችሁ ፡ ለአባቶቻች
ሁም ፡ የማለላቸውን ፡ መሐላ ፡ ስለ ፡ ጠበቀ ÷ ስለ
ዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በጽኑ ፡ እጅ ፡ አወጣችሁ ÷
ከባርነትም ፡ ቤት ፡ ከግብፅ ፡ ንጉሥ ፡ ከፈርዖን ፡
፱ ፡ እጅ ፡ አዳናችሁ ። አንተም ፡ አምላክህ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እርሱ ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ ለሚ
ወድዱትም ፡ ትእዛዙንም ፡ ለሚጠብቁ ፡ ቃል ፡
ኪዳኑንና ፡ ምሕረቱን ፡ እስከ ፡ ሺህ ፡ ትውልድ ፡
ድረስ ፡ የሚጠብቅ ፡ የታመነ ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡
፲ ፡ ሆነ ፡ እወቅ ፤ የሚጠሉትን ፡ ለማጥፋት ፡ በፊ
ታቸው ፡ ብድራት ፡ ይመልስባቸዋል ፤ ለሚጠ
ላው ፡ አይዘገይም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ በፊቱ ፡ ብድ
፲፩ ፡ ራት ፡ ይመልስበታል ። እንግዲህ ፡ ታደርጋት ፡
ዘንድ ፡ እኔ ፡ ዛሬ ፡ ለአንተ ፡ የማዝዛትን ፡ ትእዛ
ዝና ፡ ሥርዓት ፡ ፍርድንም ፡ ጠብቅ ።
፲፪ ፡ እንዲህም ፡ ይሆናል ፤ ይህችን ፡ ፍርድ ፡ ሰም
ተህ ፡ ብትጠብቃት ፡ ብታደርጋትም ÷ አምላ
ክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአባቶችህ ፡ የማለውን ፡
ቃል ፡ ኪዳንና ፡ ምሕረት ፡ ለአንተ ፡ ይጠብቅ
፲፫ ፡ ልሃል ፤ ይወድድህማል ÷ ይባርክህማል ÷ ያበ
ዛህማል ፤ ይሰጥህም ፡ ዘንድ ፡ ለአባቶችህ ፡ በማ
ለላቸው ፡ ምድር ፡ የሆድህን ፡ ፍሬ ፡ የመሬት
ህንም ፡ ፍሬ ÷ እህልህን ፡ ወይንህንም ፡ ዘይት
ህንም ÷ የከብትህንም ፡ ብዛት ፡ የበግህንም ፡
፲፬ ፡ መንጋ ፡ ይባርክልሃል ። ከአሕዛብም ፡ ሁሉ ፡
ይልቅ ፡ የተባረክህ ፡ ትሆናለህ ፤ በሰውህና ፡
በከብትህም ፡ ዘንድ ፡ ወንድ ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡
፲፭ ፡ ሴት ፡ ብትሆን ፡ መካን ፡ አይሆንብህም ። እግ
ዚአብሔርም ፡ ሕማምን ፡ ሁሉ ፡ ከአንተ ፡ ያር
ቃል ፤ የምታውቀውንም ፡ ክፉውን ፡ የግብፅ ፡
በሽታ ፡ ሁሉ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ አያደርስብህም ÷
በጠላቶችህም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያመጣባቸዋል ።
፲፮ ፡ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ በእጅህ ፡ አሳ
ልፎ ፡ የሚጥላቸውን ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ ታጠ
ፋቸዋለህ ፤ ዓይንህም ፡ አታዝንላቸውም ፤ ያም ፡
ወጥመድ ፡ ይሆንብሃልና ፡ አማልክቶቻቸውን ፡

አታምልካቸው ፡፡

፲፯ በልብህም ፡ — እነዚህ ፡ አሕዛብ ፡ ከእኔ ፡ ይልቅ ፡ ይበዛሉና ፡ አወጣቸው ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ እች ፲፰ ላለሁ ? ብትል ፤ አትፍራቸው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በፈርዖንና ፡ በግ ፲፱ ብፅ ፡ ሁሉ ፡ ያደረገውን ፤ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፤ ዓይንህ ፡ እያየች ፤ ታላቅን ፡ መቅሠፍት ፡ ምልክትንም ፡ ተአምራትንም ፡ የጸናችውን ፡ እጅ ፡ የተዘረጋውንም ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ እንዳወጣህ ፤ አስብ ፤ እንዲሁ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ አንተ ፡ በምትፈራቸው ፡ በአሕዛብ ፡ ፳ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያደርጋል ፡፡ ደግሞም ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ የቀሩት ፡ ከፊትህም ፡ የተሸሸጉት ፡ እስኪጠፉ ፡ ድረስ ፡ ተርብ ፡ ይሰድድባቸ ፳፩ ዋል ፡፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፤ ታላቅና ፡ የሚያስፈራ ፡ አምላክ ፤ በመካከልህ ፡ ነውና ፡ ፳፪ ከእነርሱ ፡ የተነሣ ፡ አትደንግጥ ፡፡ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ እነዚህን ፡ አሕዛብ ፡ በጥቂት ፡ በጥቂቱ ፡ ከፊትህ ፡ ያወጣቸዋል ፤ የምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊት ፡ እንዳይበዙብህ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ፳፫ ታጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ አይገባህም ፡፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ እነርሱን ፡ በእጅህ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣቸዋል ፤ እስኪጠፉም ፡ ድረስ ፡ በታ ፳፬ ላቅ ፡ ድንጋጤ ፡ ያስደነግጣቸዋል ፡፡ ነገሥታቶቻቸውንም ፡ በእጅህ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣቸዋል ፤ ስማቸውንም ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡ ታጠፋለህ ፤ እስክታጠፋቸው ፡ ድረስ ፡ ማንም ፡ በፊትህ ፡ ይቆም ፡ ፳፭ ዘንድ ፡ አይችልም ፡፡ የተቀረጸውንም ፡ የአምላኮቻቸውን ፡ ምስል ፡ በእሳት ፡ ታቃጥላለህ ፤ የተሠራባቸውን ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ አትመኝ ፤ በአምላክህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ርኩስ ፡ ነውና ፡ እንዳትጠመድበት ፡ ከእርሱ ፡ ምንም ፡ ፳፮ አትውሰድ ፡፡ እንደ ፡ እርሱም ፡ ርጉም ፡ እንዳትሆን ፡ ርኩስን ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ አታግባ ፤ ርጉም ፡ ነውና ፡ ተጸየፈው ፤ ጥላውም ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፰ ፡፡

፩ በሕይወት ፡ እንድትኖሩ ፤ እንድትበዙም ፤ እግዚአብሔርም ፡ ለአባቶቻችሁ ፡ ወደ ፡ ማለላቸው ፡ ምድር ፡ ገብታችሁ ፡ እንድትወርሱአት ፤ ዛሬ ፡ ለአንተ ፡ የማዝዘውን ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ፪ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ጠብቁ ፡፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይፈትንህ ፡ ዘንድ ፤ በልብህም ፡ ያለውን ፡ ትእዛዙን ፡ ትጠብቅ ፡ ወይም ፡ አትጠብቅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፤ ሊያስጨንቅህ ፡ በእነዚህ ፡ በአርባ ፡ ዓመታት ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የመራህን ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ አስብ ፡፡ ፫ ሰውም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ አፍ ፡ በሚወጣ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በሕይወት ፡ እንዲኖር ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡ በእንጀራ ፡ ብቻ ፡ በሕይወት ፡ እንዳይኖር ፡ ያስታውቅህ ፡ ዘንድ ፡ አስጨነቀህ ፤ አስራበህም ፤ አንተም ፡ ያላወቅኸውን ፡ አባቶች ፬ ህም ፡ ያላወቁትን ፡ መና ፡ አበላህ ፡፡ በእነዚህ ፡ አርባ ፡ ዓመታት ፡ የለበስኸው ፡ ልብስ ፡ አላረ ጀም ፤ እግርህም ፡ አላበጠም ፡፡ ፭ ሰውም ፡ ልጁን ፡ እንደሚገሥጽ ፡ እንዲሁም ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ አንተን ፡ እንዲገሥጽ ፡ በልብህ ፡ አስተውል ፡፡ ፮ በመንገዱም ፡ እንድትሄድ ፡ እርሱንም ፡ እንድትፈራ ፡ የአምላክህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ጠብቅ ፡፡ ፯ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ መልካም ፡ ምድር ፤ ከሸለቆና ፡ ከኮረብታ ፡ የሚመነጩ ፡ የውኃ ፡ ጅረቶችና ፡ ፈሳሾች ፡ ምንጮችም ፡ ወዳሉባት ፡ ምድር ፤ ስንዴ ፡ ገብስም ፡ ወይንም ፡ በለስም ፡ ሮማንም ፡ ፰ ወይራም ፡ ማርም ፡ ወደ ፡ ሞሉባት ፡ ምድር ፤ ሳይጐድልህ ፡ እንጀራን ፡ ወደምትበላባት ፡ አን ፱ ዳችም ፡ ወደማታጣባት ፡ ምድር ፤ ድንጋይዋ ፡ ብረት ፡ ወደ ፡ ሆነ ፤ ከተራራዋም ፡ መዳብ ፡ ወደሚገኝበት ፡ ምድር ፡ ያገባሃል ፡፡ ፲ ትበላማለህ ፤ ትጠግብማለህ ፤ ስለ ፡ ሰጠህም ፡ ስለ ፡ መልካሚቱ ፡ ምድር ፡ አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትባርካለህ ፡፡

፲፩ ዛሬ ፡ እኔ ፡ አንተን ፡ የማዝዘውን ፡ ትእዛዙንና ፡ ፍርዱን ፡ ሥርዓቱንም ፡ በለመጠበቅ ፡ አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዳትረሳ ፡ ተጠንቀቅ ፤ ፲፪ ከበላህና ፡ ከጠገብህ ፡ በኋላ ፤ መልካም ፡ ቤት ፡ ሠርተህ ፡ ከተቀመጥህበት ፡ በኋላ ፤ ፲፫ የላምና ፡ የበግ ፡ መንጋ ፡ ከበዛልህ ፡ በኋላ ፤ ብርህና ፡ ወርቅህም ፡ ያለህም ፡ ሁሉ ፡ ከበዛልህ ፡ ፲፬ በኋላ ፤ ልብህ ፡ እንዳይኰራ ፤ ከግብፅም ፡ ምድር ፡ ከባርነት ፡ ቤት ፡ ያወጣህን ፤ ፲፭ እባብና ፡ ጊንጥ ፡ ጥማትም ፡ ባለበት ፤ ውኃም ፡ በሌለበት ፤ በታላቂቱና ፡ በምታስፈራው ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ የመራህን ፤ ከጭንጫ ፡ ድንጋይም ፡ ውኃን ፡ ያወጣልህን ፤ ፲፮ በመጨረሻም ፡ ዘመን ፡ መልካም ፡ ያደርግልህ ፡ ዘንድ ፡ ሊፈትንህ ፡ ሊያዋርድህም ፡ አባቶችህ ፡ ያላወቁትን ፡ መና ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ያበላህን ፡ አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዳ ፲፯ ትረሳ ፤ በልብህም ፡ — ጉልበቴ ፡ የእጄም ፡ ብርታት ፡ ይህን ፡ ሀብት ፡ አመጣልኝ ፡ እንዳትል ፡፡ ፲፰ ነገር ፡ ግን ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለአባቶችህ ፡ የማለውን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ያጸና ፡ ዘንድ ፤ ሀብት ፡ ለማከማቸት ፡ እርሱ ፡ ጉልበት ፡ ሰጥቶሃልና ፡ አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አስብ ፡፡ ፲፱ አምላክህንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ብትረሳ ፤ ሌሎችንም ፡ አማልክት ፡ ብትከተል ፡ ብታመልካቸውም ፡ ብትሰግድላቸውም ፤ ፈጽሞ ፡ እንድትጠፉ ፡ እኔ ፡ ዛሬውኑ ፡ እመሰክርባችኋለሁ ፡፡ ፳ የአምላካችሁን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስላልሰማችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከፊታችሁ ፡ እንደሚያጠፋቸው ፡ እንደ ፡ አሕዛብ ፡ እንዲሁ ፡ እናንተ ፡ ትጠፋላችሁ ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፱ ፡፡

፩ እስራኤል ፡ ሆይ ፤ ስማ ፤ ከአንተ ፡ የበለጡትንና ፡ የበረቱትን ፡ አሕዛብ ፤ እስከ ፡ ሰማይም ፡ ድረስ ፡ የተመሸጉትን ፡ ታላላቆች ፡ ከተሞች ፡ ለመውረስ ፡ ትገቡ ፡ ዘንድ ፡ ዛሬ ፡ ዮርዳኖስን ፡

፪ ትሸገረዋለህ ። አንተም ፡ የምታውቃቸው ፡
ስለ ፡ እነርሱም ፡— በዔናቅ ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡
መቆም ፡ ማን ፡ ይችላል ? ሲባል ፡ የሰማኸው ፡
ታላቁና ፡ ረጅሙ ፡ ሕዝብ ፡ የዔናቅ ፡ ልጆች ፡
፫ ናቸው ። አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ
ሚበላ ፡ እሳት ፡ ሆኖ ፡ በፊትህ ፡ እንዲያልፍ ፡ ዛሬ ፡
እወቅ ፤ እርሱ ፡ ያጠፋቸዋል ፥ በፊትህም ፡
ያዋርዳቸዋል ፤ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ነገ
ረህ ፡ አንተ ፡ ታሳድዳቸዋለህ ፥ ፈጥነህም ፡ ታጠ
፬ ፋቸዋለህ ። አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከፊ
ትህ ፡ ካወጣቸው ፡ በኋላ ፡— ስለ ፡ ጽድቄ ፡ እወ
ርሳት ፡ ዘንድ ፡ ወደዚች ፡ ምድር ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ አገባኝ ፡ ስትል ፡ በልብህ ፡ አትናገር ፤ እነ
ዚህን ፡ አሕዛብ ፡ ስለ ፡ ኃጢአታቸው ፡ እግዚአ
፭ ብሔር ፡ ከፊትህ ፡ ያወጣቸዋል ። ምድራቸውን ፡
ትወርሳት ፡ ዘንድ ፡ የምትገባው ፡ ስለ ፡ ጽድቅ
ህና ፡ ስለ ፡ ልብህ ፡ ቅንነት ፡ አይደለም ፤ ነገር ፡
ግን ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከፊትህ ፡ በሚ
ያጠፋቸው ፡ በእነዚያ ፡ አሕዛብ ፡ ኃጢአት ፡ ምክ
ንያትና ፡ ለአባቶችህ ፡ ለአብርሃምና ፡ ለይስሐቅ ፡
ለያዕቆብም ፡ የማለላቸውን ፡ ቃል ፡ ይፈጽም ፡
፮ ዘንድ ፡ ነው ። እንግዲህ ፡ አንተ ፡ አንገተ ፡ ደን
ዳና ፡ ሕዝብ ፡ ነህና ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡
ይህችን ፡ መልካም ፡ ምድር ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡
የሰጠህ ፡ ስለ ፡ ጽድቅህ ፡ እንዳይደለ ፡ እወቅ ።
፯ አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡
እንዳስቈጣኸው ፤ ከግብፅ ፡ አገር ፡ ከወጣህበት ፡
ቀን ፡ ጀምሮ ፡ ወደዚህ ፡ ስፍራ ፡ እስከ ፡ መጣ
ችሁ ፡ ድረስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ እንዳመ
፰ ፀችሁ ፡ አስብ ፥ አትርሳ ። በኮሬብ ፡ ደግሞ ፡
እግዚአብሔርን ፡ አስቈጣችሁ ፤ እግዚአብሔ
፱ ርም ፡ ሊያጠፋችሁ ፡ ተቈጣባችሁ ። የድንጋዩን ፡
ጽላቶች ፥ እግዚአብሔር ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ የተ
ማማለበቸውን ፡ የቃል ፡ ኪዳን ፡ ጽላቶች ፥ እቀ
በል ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ተራራ ፡ በወጣሁ ፡ ጊዜ ፥
በተራራው ፡ አርባ ፡ ቀንና ፡ አርባ ፡ ሌሊት ፡ ተቀ
ምጬ ፡ ነበር ፤ እንጀራ ፡ አልበላሁም ፥ ውኃም ፡
፲ አልጠጣሁም ። እግዚአብሔርም ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ጣት ፡ የተጻፉትን ፡ ሁለት ፡ የድንጋይ ፡
ጽላቶች ፡ ሰጠኝ ፤ ስብሰባ ፡ ተደርጎ ፡ በነበረበ
ትም ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ በተራራው ፡ ላይ ፡
በእሳት ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ የነገራችሁ ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡
፲፩ ተጽፎባቸው ፡ ነበር ። ከአርባ ፡ ቀንና ፡ ከአርባ ፡
ሌሊትም ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሁለቱን ፡ የድ
ንጋይ ፡ ጽላቶች ፥ የቃል ፡ ኪዳኑን ፡ ጽላቶች ፥
፲፪ ሰጠኝ ። እግዚአብሔርም ፡— ተነሥተህ ፡ ከዚህ ፡
ፈጥነህ ፡ ውረድ ፤ ከግብፅ ፡ ያወጣሃቸው ፡ ሕዝ
ብህ ፡ ረከሰዋል ፤ ፈጥነው ፡ ካዘዝኋቸው ፡ መን
ገድ ፡ ፈቀቅ ፡ ብለዋል ፥ ቀልጦ ፡ የተሠራ ፡ ምስ
፲፫ ልም ፡ ለራሳቸው ፡ አድርገዋል ፡ አለኝ ። እግ
ዚአብሔርም ፡— ይህ ፡ ሕዝብ ፡ አንገተ ፡ ደን
፲፬ ዳና ፡ ሕዝብ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አይቼአለሁ ፤ አጠ
ፋቸው ፡ ዘንድ ፥ ስማቸውንም ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡
እደመስስ ፡ ዘንድ ፡ ተወኝ ፤ አንተንም ፡ ከእነ
ርሱ ፡ ለሚበረታና ፡ ለሚበዛ ፡ ሕዝብ ፡ አደርግ
፲፭ ሃለሁ ፡ ብሎ ፡ ተናገረኝ ። እኔም ፡ ተመልሼ ፡
ከተራራው ፡ ወረድሁ ፥ ተራራውም ፡ በእሳት ፡
ይነድድ ፡ ነበር ፤ ሁለቱም ፡ የቃል ፡ ኪዳን ፡
፲፮ ጽላቶች ፡ በሁለቱ ፡ እጆቼ ፡ ነበሩ ። ተመለከት
ሁም ፤ እነሆ ፥ አምላካችሁን ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ በድላችሁ ፡ ነበር ፥ ለእናንተም ፡ ቀልጦ ፡
የተሠራ ፡ የጥጃ ፡ ምስል ፡ ሠርታችሁ ፡ ነበር ፤
እግዚአብሔር ፡ ካዘዛችሁ ፡ መንገድ ፡ ፈጥና
፲፯ ችሁ ፡ ፈቀቅ ፡ ብላችሁ ፡ ነበር ። ሁለቱንም ፡
ጽላቶች ፡ ያዝሁ ፥ ከሁለቱም ፡ እጆቼ ፡ ጣል
ኋቸው ፥ እናንተም ፡ ስታዩ ፡ ሰበርኋቸው ።
፲፰፲፱ ስለ ፡ ሠራችሁት ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፥ እርሱንም ፡
ለማስቈጣት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡
የሆነውን ፡ ነገር ፡ ስላደረጋችሁ ፥ እግዚአብ
ሔር ፡ ሊያጠፋችሁ ፡ ከተቈጣባችሁ ፡ ከቍጣ
ውና ፡ ከመዓቱ ፡ የተነሣ ፡ ስለ ፡ ፈራሁ ፥ እንደ ፡
ፊተኛው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አርባ ፡ ቀንና ፡
አርባ ፡ ሌሊት ፡ ወደቅሁ ፤ እንጀራ ፡ አልበላ
ሁም ፥ ውኃም ፡ አልጠጣሁም ። እግዚአብሔ
ርም ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ደግሞ ፡ ሰማኝ ። እግዚ
፳ አብሔርም ፡ አሮንን ፡ ሊያጠፋው ፡ እጅግ ፡ ተቈ
ጣው ፤ ስለ ፡ አሮንም ፡ ደግሞ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡
፳፩ ጸለይሁ ። ያደረጋችሁትንም ፡ ኃጢአት ፡ ጥጃ
ውን ፡ወሰድሁ ፥ በእሳትም ፡ አቃጠልሁት ፥
አደቀቅሁትም ፥ እንደ ፡ ትቢያም ፡ እስኪሆን ፡
ድረስ ፡ ፈጨሁት ፤ ትቢያውንም ፡ ከተራራ ፡
በሚወርድ ፡ ወንዝ ፡ ጣልሁት ።
፳፪ በተቤራም ፡ በማሳህም ፡ በምኞት ፡ መቃብ
፳፫ ርም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አስቈጣችሁት ። እግ
ዚአብሔርም ፡— ውጡ ፡ የሰጠኋችሁንም ፡
ምድር ፡ ውረሱ ፡ ብሎ ፡ ከቃዴስ ፡ በርኔ ፡ በላካ
ችሁ ፡ ጊዜ ፥ በአምላካችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ ዐመፃችሁ ፥ በእርሱም ፡ አላመናችሁም ፥
፳፬ ድምፁንም ፡ አልሰማችሁም ። እናንተን ፡ ካወቅ
ሁበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዓመፀ
ኞች ፡ ነበራችሁ ።
፳፭ እግዚአብሔርም ፡— አጠፋችኋለሁ ፡ ብሎ ፡
ስለ ፡ ተናገረ ፡ በወደቅሁበት ፡ ዘመን ፡ አርባ ፡
ቀንና ፡ አርባ ፡ ሌሊት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
፳፮ ወደቅሁ ። በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ እንዲህ ፡
ብዬ ፡ ጸለይሁ ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥
በታላቅነትህ ፡ የተቤዠኸውን ፥ በጠነከረች
ውም ፡ እጅ ፡ ከግብፅ ፡ ያወጣኸውን ፡ ሕዝብህ
፳፯ ንና ፡ ርስትህን ፡ አታጥፋ ። ባሪያዎችህን ፡ አብርሃ
ምንና ፡ ይስሐቅን ፡ ያዕቆብንም ፡ አስብ ፤ የዚህን ፡
ሕዝብ ፡ ደንዳንነት ፡ ክፋቱንም ፡ ኃጢአቱንም ፡
፳፰ አትመልከት ፤ ከእርስዋ ፡ እኛን ፡ ያወጣህበት ፡
ምድር ፡ ሰዎች ፡— እግዚአብሔር ፡ ተስፋ ፡ ወደ ፡
ሰጣቸው ፡ ምድር ፡ ያገባቸው ፡ ዘንድ ፡ አልቻለ
ምና ፥ ጠልቶአቸውማልና ፡ ስለዚህ ፡ በምድረ ፡
በዳ ፡ ሊገድላቸው ፡ አወጣቸው ፡ እንዳይሉ ። እነ
፳፱ ርሱም ፡ በታላቅ ፡ ኃይልህ ፡ በተዘረጋውም ፡ ክን
ድህ ፡ያወጣሃቸው ፡ ሕዝብህና ፡ ርስትህ ፡ ናቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡— እንደ ፡
ፊተኞች ፡ ያሉትን ፡ ሁለት ፡ የድንጋይ ፡ ጽላ
ቶች ፡ ጠርበህ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ወደ ፡ ተራራው ፡
ውጣ ፤ ለአንተም ፡ የእንጨት ፡ ታቦት ፡ ሥራ ፤
፪ በሰበርሃቸውም ፡ በፊተኞቹ ፡ ጽላቶች ፡ የነበሩ
ትን ፡ ቃሎች ፡ በእነዚህ ፡ ጽላቶች ፡ እጽፋለሁ ፤
በታቦቱም ፡ ውስጥ ፡ ታደርጋቸዋለህ ፡ አለኝ ።
፫ ከግራርም ፡ እንጨት ፡ ታቦትን ፡ ሠራሁ ፤ እንደ ፡
ፊተኞችም ፡ ሁለት ፡ የድንጋይ ፡ ጽላቶች ፡ ጠረ
ብሁ ፤ ሁለቱንም ፡ ጽላቶች ፡ በእጄ ፡ ይዤ ፡ ወደ ፡
፬ ተራራው ፡ ወጣሁ ። ስብሰባ ፡ ተደርጎ ፡ በነበረበ
ትም ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ በተራራው ፡ ላይ ፡
በእሳት ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ የተናገራችሁን ፡ አሠ
ርቱን ፡ ቃላት ፡ ቀድሞ ፡ ተጽፈው ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡
በጽላቶቹ ፡ ላይ ፡ ጻፈ ፤ እግዚአብሔርም ፡ እነር
፭ ሱን ፡ ለእኔ ፡ ሰጠኝ ። ተመልሼም ፡ ከተራራው ፡
ወረድሁ ፤ ጽላቶችንም ፡ በሠራሁት ፡ ታቦት ፡
ውስጥ ፡ አደረግኋቸው ፤ እግዚአብሔርም ፡ እን
ዳዘዘኝ ፡ በዚያ ፡ ኖሩ ።
፮ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከብኤሮት ፡ ብኔያዕ
ቃን ፡ ወደ ፡ ሞሴራ ፡ ተጓዙ ፤ በዚያም ፡ አሮን ፡
ሞተ ፡ በዚያም ፡ ተቀበረ ፤ በእርሱም ፡ ፋንታ ፡
፯ ልጁ ፡ አልዓዛር ፡ ካህን ፡ ሆነ ። ከዚያም ፡ ወደ ፡
ጉድጎዳ ፡ ተጓዙ ፤ ከጉድጎዳም ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡
፰ ፈሳሾች ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ ዮጥባታ ፡ ተጓዙ ። በዚ
ያን ፡ ጊዜ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
ታቦት ፡ ይሸከም ፡ ዘንድ ፤ እርሱንም ፡ ለማገል
ገል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይቆም ፡ ዘንድ ፤
በስሙም ፡ ይባርክ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡
፱ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ የሌዊን ፡ ነገድ ፡ ለየ ። ስለ
ዚህ ፡ ለሌዊ ፡ ከወንድሞቹ ፡ ጋር ፡ ክፍልና ፡
ርስት ፡ የለውም ፤ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡
እንደ ፡ ተናገረው ፡ እግዚአብሔር ፡ ርስቱ ፡ ነው ።
፲ እኔም ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ ጊዜ ፡ አርባ ፡ ቀንና ፡
አርባ ፡ ሌሊት ፡ በተራራው ፡ ላይ ፡ ተቀመጥሁ ፤
እግዚአብሔርም ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ደግሞ ፡ ሰማኝ ፤
፲፩ እግዚአብሔር ፡ ሊያጠፋህ ፡ አልወደደም ። እግ
ዚአብሔርም ፡— ተነሥተህ ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡
ተጓዝ ፤ ለአባቶቻቸውም ፡ ልሰጣቸው ፡ ወደ ፡
ማልሁላቸው ፡ ምድር ፡ ይግቡ ፡ ይውረሱአ
ትም ፡ አለኝ ።
፲፪፣፲፫ እስራኤል ፡ ሆይ ፤ አሁንስ ፡ አምላክህን ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ ትፈራ ፡ ዘንድ ፤ በመንገዱም ፡
ሁሉ ፡ ትሄድ ፡ ዘንድ ፤ አምላክህንም ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ ትወድድ ፡ ዘንድ ፤ በፍጹምም ፡ ልብህ ፡
በፍጹምም ፡ ነፍስህ ፡ ታመልከው ፡ ዘንድ ፤ መል
ካምም ፡ እንዲሆንልህ ፡ ዛሬ ፡ ለአንተ ፡ የማዝዘ
ውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝና ፡ ሥርዓት ፡
ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ አምላክህ ፡
እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ የሚፈልገው ፡ ምን
፲፬ ድር ፡ ነው ? እነሆ ፤ ሰማይ ፡ ሰማየ ፡ ሰማያትም ፤
ምድርም ፡ በእርስዋም ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ የአምላ
ክህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነው ። ብቻ ፡ እግዚአብ ፲፭
ሔር ፡ ስለ ፡ አባቶችህ ፡ ደስ ፡ ብሎታል ፤ እነር
ሱንም ፡ ወድዶአል ፤ ከእነርሱም ፡ በኋላ ፡ እናን
ተን ፡ ዘራቸውን ፡ እንደ ፡ ዛሬው ፡ ሁሉ ፡ ከአሕ
ዛብ ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ መረጠ ። እንግዲህ ፡ አም ፲፮፣፲፯
ላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ የአማልክት ፡ አም
ላክ ፡ የጌቶችም ፡ ጌታ ፤ ታላቅ ፡ አምላክ ፡ ኃያ
ልም ፡ የሚያስፈራም ፤ በፍርድ ፡ የማያደላ ፤
መማለጃም ፡ የማይቀበል ፡ ነውና ፡ እናንተ ፡
የልባችሁን ፡ ሸለፈት ፡ ግረዙ ፤ ከእንግዲህ ፡
ወዲህም ፡ አንገተ ፡ ደንዳና ፡ አትሁኑ ። ለድሀ ፡ ፲፰
አደጉና ፡ ለመበለቲቱ ፡ ይፈርዳል ፤ መብልና ፡
ልብስም ፡ ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡ ስደተኛውን ፡ ይወ
ድዳል ። እናንተ ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ ስደተኞች ፡ ፲፱
ነበራችሁና ፡ ስለዚህ ፡ ስደተኛውን ፡ ውደዱ ።
አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፍራ ፤ እርሱንም ፡ ፳
አምልክ ፤ ከእርሱም ፡ ተጣበቅ ፤ በስሙም ፡
ማል ። ዓይኖችህ ፡ ያዩትን ፡ እነዚህን ፡ ታላላ ፳፩
ቆች ፡ የሚያስፈሩትንም ፡ ነገሮች ፡ ያደረገልህ ፡
እርሱ ፡ ክብርህ ፡ ነው ፤ እርሱም ፡ አምላክህ ፡
ነው ። አባቶችህ ፡ ሰባ ፡ ነፍስ ፡ ሆነው ፡ ወደ ፡ ፳፪
ግብፅ ፡ ወረዱ ፤ አሁንም ፡ አምላክህ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ብዛትህን ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከዋክብት ፡
አደረገ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

እንግዲህ ፡ አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፩
ውደድ ፤ ሕጉንም ፡ ሥርዓቱንም ፡ ፍርዱንም ፡
ትእዛዙንም ፡ ሁልጊዜ ፡ ጠብቅ ። የአምላካች ፪
ሁን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ተግሣጽ ፤ ታላቅነቱ
ንም ፤ የጸናችም ፡ እጁን ፤ የተዘረጋውንም ፡ ክን
ዱን ፤ በግብፅም ፡ መካከል ፡ በንጉሡ ፡ በፈርዖ ፫
ንና ፡ በአገሩ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያደረጋትን ፡ ተአም
ራቱንና ፡ ሥራውን ፤ በተከተሉአችሁም ፡ ጊዜ ፡ ፬
በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ ውኃ ፡ እንዳሰጠማቸው ፤
እግዚአብሔርም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እንዳጠ
ፋቸው ፤ በግብፅ ፡ ጭፍራ ፡ በፈረሶቻቸውም ፡
በሰረገሎቻቸውም ፡ ያደረገውን ፤ ወደዚህ ፡ ፭
ስፍራ ፡ እስክትመጡ ፡ ድረስ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡
ያደረገላችሁን ፤ በእስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ መካ ፮
ከል ፡ ምድር ፡ አፍዋን ፡ ከፍታ ፡ እነርሱንና ፡
ቤተ ፡ ሰቦቻቸውን ፡ ድንኳኖቻቸውንም ፡ ለእነ
ርሱም ፡ የነበራቸውን ፡ ሁሉ ፡ በዋጠቻቸው ፡
በሮቤል ፡ ልጅ ፡ በኤልያብ ፡ ልጆች ፡ በዳታንና ፡
በአቤሮን ፡ ያደረገውን ፡ ላላወቁትና ፡ ላላዩት ፡
ልጆቻችሁ ፡ አልነግራቸውምና ፡ እናንተ ፡ ዛሬ ፡
እወቁ ። ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ያደረጋ ፯
ትን ፡ ታላቂቱን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ዓይኖቻችሁ ፡
አይተዋል ።
እንግዲህ ፡ እንድትጠነክሩ ፤ ትወርሱአትም ፡ ፰፣፱
ዘንድ ፡ ወደምትሻገሩባት ፡ ምድር ፡ እንድትገቡ ፡
እንድትወርሱአትም ፤ እግዚአብሔርም ፡ ለእነ
ርሱና ፡ ለዘራቸው ፡ ይሰጣት ፡ ዘንድ ፡ በማለላ
ቸው ፡ ወተትና ፡ ማርም ፡ በምታፈስሰው ፡ ምድር ፡

ዕድሜአችሁ ፡ እንዲረዝም ፥ ዛሬ ፡ ለእናንተ ፡ የማዝዘውን ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ጠብቁ ። ፲ ትወርሳት ፡ ዘንድ ፡ የምትገባባት ፡ ምድር ፥ በአትክልት ፡ ስፍራ ፡ እንደሚዘሩ ፡ ዘርህን ፡ እንደ ፡ ዘራህባት ፥ በእግርህም ፡ እንዳጠጣሃት ፥ እንደ ፡ ወጣህባት ፡ እንደ ፡ ግብፅ ፡ ምድር ፡ አይደለችም ። ፲፩ ነገር ፡ ግን ፡ ትወርሱአት ፡ ዘንድ ፡ ተሻግራችሁ ፡ የምትገቡባት ፡ ምድር ፡ ኮረብታና ፡ ሸለቆ ፡ ያለባት ፡ አገር ፡ ናት ፤ በሰማይ ፡ ዝናብ ፡ ውኃ ፡ ፲፪ ትረካለች ። አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚጐበኛት ፡ አገር ፡ ናት ፤ ከዓመቱ ፡ መጀመሪያ ፡ እስከ ፡ ዓመቱ ፡ መጨረሻ ፡ ድረስ ፡ የአምላክህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ዓይን ፡ ሁልጊዜ ፡ በእርስዋ ፡ ላይ ፡ ነው ።

፲፫ እንዲህም ፡ ይሆናል ፤ እናንተ ፡ አምላካችሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትወድዱ ፡ ዘንድ ፥ በፍጹምም ፡ ልባችሁ ፡ በፍጹምም ፡ ነፍሳችሁ ፡ ታመልኩት ፡ ዘንድ ፡ ዛሬ ፡ ለእናንተ ፡ የማዝዘውን ፡ ትእዛዜን ፡ ፈጽማችሁ ፡ ብትሰሙ ፥ ፲፬ እህልህን ፡ ወይንህንም ፡ ዘይትህንም ፡ ትሰበስብ ፡ ዘንድ ፡ በየጊዜው ፡ የበልጉን ፡ ዝናብና ፡ የክረምቱን ፡ ዝናብ ፡ ለምድራችሁ ፡ አወርዳለሁ ። ፲፭ በሜዳ ፡ ለእንስሶችህ ፡ ሣርን ፡ እሰጣለሁ ፥ ፲፮ ትበላማለህ ፥ ትጠግብማለህ ። ልባችሁ ፡ እንዳይስት ፥ ፈቀቅ ፡ እንዳትሉ ፥ ሌሎችንም ፡ አማልክት ፡ እንዳታመልኩ ፥ እንዳትሰግዱላ ፲፯ ቸውም ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ እንዳይነድድባችሁ ፥ ዝናብም ፡ እንዳይዘንብ ፡ ምድሪቱም ፡ ፍሬዋን ፡ እንዳትሰጥ ፡ ሰማይን ፡ እንዳይዘጋባችሁ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ከሚሰጣችሁ ፡ ከመልካሚቱ ፡ ምድር ፡ ፈጥናችሁ ፡ እንዳትጠፉ ፡ ተጠንቀቁ ።

፲፰ እንግዲህ ፡ እነዚህን ፡ ቃሎች ፡ በልባችሁና ፡ በነፍሳችሁ ፡ አኑሩ ፤ እነርሱንም ፡ ለምልክት ፡ በእጃችሁ ፡ ላይ ፡ እሰሩአቸው ፥ በዓይኖቻችሁም ፡ ፲፱ መካከል ፡ እንደ ፡ ክታብ ፡ ይሁኑ ። ልጆቻችሁንም ፡ አስተምሩአቸው ፥ በቤትህም ፡ ስትቀመጥ ፥ በመንገድም ፡ ስትሄድ ፥ ስትተኛም ፡ ስትነሣም ፡ ፳፩ አጫውቱአቸው ። እርስዋንም ፡ እንዲሰጣቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአባቶቻችሁ ፡ በማለላቸው ፡ ምድር ፥ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ዘመን ፡ በምድር ፡ ላይ ፥ ዘመናችሁ ፡ የልጆቻችሁም ፡ ዘመን ፡ ይረዝም ፡ ዘንድ ፡ በቤትህ ፡ መቃኖችና ፡ በደጃ ፳፪ ፍህም ፡ በሮች ፡ ላይ ፡ ጻፈው ። አምላካችሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትወድዱ ፡ ዘንድ ፥ በመንገዱም ፡ ሁሉ ፡ ትሄዱ ፡ ዘንድ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ትጣበቁ ፡ ዘንድ ፥ ዛሬ ፡ ለእናንተ ፡ የማዝዘውን ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ብትጠብቁ ፡ ብታደርጉአትም ፥ ፳፫ እግዚአብሔር ፡ እነዚህን ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ከፊታችሁ ፡ ያወጣል ፥ ከእናንተም ፡ የሚበልጡትን ፡ የሚበረቱትንም ፡ አሕዛብ ፡ ትወርሳላችሁ ። ፳፬ የእግራችሁ ፡ ጫማ ፡ የምትረግጣት ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ ለእናንተ ፡ ትሆናለች ፤ ከምድረ ፡ በዳም ፡ ከሊባኖስም ፡ ከታላቁም ፡ ከኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፡ ዳርቻችሁ ፡ ይሆናል ። ፳፭ በእናንተም ፡ ፊት ፡ ማንም ፡ መቆም ፡ አይችልም ፤ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፥ እርሱ ፡ እንደ ፡ ተናገራችሁ ፥ ማስፈራታችሁን ፡ ማስደንገጣችሁንም ፡ በምትረግጡአት ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያኖራል ።

፳፮ እነሆ ፥ እኔ ፡ ዛሬ ፡ በፊታችሁ ፡ በረከትንና ፡ ፳፯ መርገምን ፡ አኖራለሁ ፤ በረከትም ፥ እኔ ፡ ዛሬ ፡ ለእናንተ ፡ የማዝዘውን ፡ የአምላካችሁን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ብትሰሙ ፤ ፳፰ መርገምም ፥ የአምላካችሁን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ባትሰሙ ፥ ዛሬም ፡ ከማዝዛችሁ ፡ መንገድ ፡ ፈቀቅ ፡ ብትሉ ፥ ሌሎችንም ፡ የማታውቋቸውን ፡ አማልክት ፡ ብትከተሉ ፡ ነው ። ፳፱ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ትወርሳት ፡ ዘንድ ፡ አንተን ፡ ወደምትሄድባት ፡ ምድር ፡ ባገባህ ፡ ጊዜ ፥ በረከቱን ፡ በገሪዛን ፡ ተራራ ፡ መርገሙንም ፡ በጌባል ፡ ተራራ ፡ ታኖራለህ ። ፴ እነርሱም ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፥ ከፀሐይ ፡ መግቢያ ፡ ካለችው ፡ መንገድ ፡ በኋላ ፥ በዓረባ ፡ በተቀመጡት ፡ በከነዓናውያን ፡ ምድር ፥ በጌልገላ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በሞሬ ፡ የአድባር ፡ ዛፍ ፡ አጠገብ ፡ ናቸው ። ፴፩ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚሰጣችሁን ፡ ምድር ፡ ትወርሱ ፡ ዘንድ ፡ ዮርዳኖስን ፡ ትሻገራላችሁ ፥ ትወርሱአታላችሁም ፥ ትቀመጡባታላችሁም ። ፴፪ እኔም ፡ ዛሬ ፡ በፊታችሁ ፡ የማኖራትን ፡ ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ ሁሉ ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ጠብቁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ በምድር ፡ ላይ ፡ በምትኖሩበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ የአባቶቻችሁ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለመውረስ ፡ በሰጣችሁ ፡ አገር ፥ የምትጠብቁአትና ፡ የምታደርጉአት ፡ ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። ፪ እናንተ ፡ የምትወርሱአቸው ፡ አሕዛብ ፡ አማልክቶቻቸውን ፡ ያመለኩባቸውን ፡ በረጅም ፡ ተራሮች ፡ በኮረብቶችም ፡ ላይ ፡ ከለምለምም ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ ያለውን ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ ፈጽማችሁ ፡ አጥፉአቸው ፤ ፫ መሠዊያቸውንም ፡ አፍርሱ ፥ ሐውልቶቻቸውንም ፡ ሰባብሩ ፥ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶቻቸውንም ፡ በእሳት ፡ አቃጥሉ ፥ የአማልክቶቻቸውንም ፡ የተቀረጹ ፡ ምስሎች ፡ አንከታክቱ ፤ ከዚያም ፡ ስፍራ ፡ ስማቸውን ፡ አጥፉ ። ፬ ለአምላካችሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡ አትሥሩ ። ፭ ነገር ፡ ግን ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከነገዶቻችሁ ፡ ሁሉ ፡ ስሙን ፡ በዚያ ፡ ያኖር ፡ ዘንድ ፡ ወደዚያ ፡ ወደ ፡ መረጠው ፡ ስፍራ ፡ ትመጣላችሁ ፥ ማደሪያውንም ፡ ትሻላችሁ ። ፮ ወደዚያም ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕታችሁን ፥ ሌላ ፡ መሥዋዕታችሁንም ፥ አሥራታችሁንም ፥ በእጃችሁም ፡ ያነሣችሁትን ፡ ቍርባን ፥ ስእለታችሁንም ፥ በፈቃዳችሁ ፡ የምታቀርቡትን ፥ የላማችሁንና ፡ የበጋችሁንም ፡ በኵራት ፡ ውሰዱ ። ፯ በዚያም ፡ በአ

ምላካችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ብሉ ፣ እጃ
ችሁንም ፡ በምትዘረጉበት ፣ አምላክህ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ በባረከህ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፣ እናንተና ፡
፰ ቤት ፡ ሰባችሁ ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ። ሰው ፡ ሁሉ ፡
በፊቱ ፡ መልካም ፡ መስሎ ፡ የታየውን ፣ እኛ ፡
በዚህ ፡ ዛሬ ፡ የምናደርገውን ፡ ሁሉ ፡ አታደር
፱ ጉም ፤ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደሚ
ሰጣችሁ ፡ ዕረፍትና ፡ ርስት ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡
፲ አልገባችሁምና ። ዮርዳኖስን ፡ ግን ፡ በተሻገራ
ችሁ ፡ ጊዜ ፣ አምላካችሁም ፡ እግዚአብሔር ፡
በሚያወርሳችሁ ፡ ምድር ፡ በተቀመጣችሁ ፡
ጊዜ ፣ ያለ ፡ ፍርሃትም ፡ እንድትኖሩ ፡ ከከበቡ
አችሁ ፡ ጠላቶች ፡ ሁሉ ፡ ዕረፍት ፡ በሰጣችሁ ፡
፲፩ ጊዜ ፣ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ስሙ ፡ ይጠራበት ፡ ዘንድ ፡ ወደዚያ ፡
ወደ ፡ መረጠው ፡ ስፍራ ፣ እኔ ፡ የማዝዛችሁን ፡
ሁሉ ፣ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕታችሁን ፣
ሌላ ፡ መሥዋዕታችሁንም ፣ አሥራታችሁንም ፣
በእጃችሁ ፡ ያነሣችሁትንም ፡ ቍርባን ፣ ለእግዚ
አብሔርም ፡ ተስላችሁ ፡ የመረጣችሁትን ፡ ስእ
፲፪ ለታችሁን ፡ ሁሉ ፡ ውሰዱ ። እናንተም ፣ ወን
ዶች ፡ ልጆቻችሁና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችሁም ፣
ባሪያዎቻችሁም ፣ ገረዶቻችሁም ፣ ከእናንተ ፡
ጋር ፡ ክፍልና ፡ ርስት ፡ ስለሌለው ፡ በደጆቻ
ችሁ ፡ ውስጥ ፡ የተቀመጠው ፡ ሌዋዊም ፡ በአም
ላካችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ደስ ፡ ይበላ
፲፫ ችሁ ። የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትህን ፡ በሚ
ታይህ ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ እንዳታቀርብ ፡ ተጠን
፲፬ ቀቅ ። ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ከነገዶችህ ፡
ከአንዱ ፡ ዘንድ ፡ በመረጠው ፡ ስፍራ ፡ በዚያ ፡
የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትህን ፡ አቅርብ ፣ በዚ
ያም ፡ የማዝዝህን ፡ ሁሉ ፡ አድርግ ።

፲፭ ነገር ፡ ግን ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡
ሰጠህ ፡ በረከት ፣ ሰውነትህ ፡ እንደ ፡ ፈቀደ ፣
በደጆችህ ፡ ሁሉ ፡ ውስጥ ፡ አርደህ ፡ ብላ ፤ ንጹሕ ፡
ሰው ፡ ንጹሕም ፡ ያልሆነ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሚዳ
፲፮ ቋና ፡ እንደ ፡ ዋላ ፡ ያለውን ፡ ይብላው ። ደሙን ፡
ግን ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አፍስሰው ፡
፲፯ እንጂ ፡ አትብላው ። የእህልህን ፡ የወይን ፡ ጠጅ
ህን ፡ የዘይትህንም ፡ አሥራት ፣ የላምህንና ፡
የበግህንም ፡ በኵራት ፣ የተሳልኸውንም ፡ ስእ
ለት ፡ ሁሉ ፣ በፈቃድህም ፡ ያቀረብኸውን ፣
በእጅህም ፡ ያነሣኸውን ፡ ቍርባን ፡ በደጆችህ
፲፰ ውስጥ ፡ መብላት ፡ አትችልም ። ነገር ፡ ግን ፡
አንተ ፣ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆችህም ፣ ባሪ
ያዎችህና ፡ ገረዶችህም ፣ በአገርህም ፡ ደጅ ፡
ያለው ፡ ሌዋዊ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡
በመረጠው ፡ ስፍራ ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ፊት ፡ ብሉት ፤ እጅህንም ፡ በምትዘረጋ
በት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡
፲፱ ፊት ፡ ደስ ፡ ይበልህ ። በምድርህ ፡ ላይ ፡ በም
ትኖርበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ሌዋዊውን ፡ ቸል ፡
እንዳትል ፡ ተጠንቀቅ ።

፳ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ነገረህ ፡
አገርህን ፡ በሰፋ ፡ ጊዜ ፣ ሰውነትህም ፡ ሥጋ ፡
መብላት ፡ ስለ ፡ ወደደች ፡— ሥጋ ፡ ልብላ ፡
ስትል ፣ እንደ ፡ ሰውነትህ ፡ ፈቃድ ፡ ሥጋን ፡
፳፩ ብላ ። አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚያ ፡ ስሙን ፡
ያኖር ፡ ዘንድ ፡ የመረጠው ፡ ስፍራ ፡ ከአንተ ፡
ሩቅ ፡ ቢሆንም ፣ እግዚአብሔር ፡ ከሰጠህ ፡ ከላ
ምና ፡ ከበግ ፡ መንጋህ ፡ እንዳዘዝሁህ ፡ እረድ ፣
እንደ ፡ ሰውነትህም ፡ ፈቃድ ፡ ሁሉ ፡ በአገርህ ፡
፳፪ ደጅ ፡ ውስጥ ፡ ብላው ። ሚዳቋና ፡ ዋላ ፡ እንደሚ
በሉ ፡ እንዲሁ ፡ ብላው ፤ ንጹሕ ፡ ሰው ፡ ንጹሕም ፡
፳፫ ያልሆነ ፡ ይብላው ። ነገር ፡ ግን ፡ ደሙ ፡ ነፍሱ ፡
ነውና ፣ ነፍሱንም ፡ ከሥጋው ፡ ጋር ፡ መብላት ፡
አይገባህምና ፡ ደሙን ፡ እንዳትበላ ፡ ተጠንቀቅ ።
፳፬ በምድር ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ አፍስሰው ፡ እንጂ ፡
፳፭ አትብላው ። በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ መልካም ፡
የሆነውን ፡ ነገር ፡ ስታደርግ ፡ ለአንተ ፡ ከአንተም ፡
በኋላ ፡ ለልጆችህ ፡ መልካም ፡ እንዲሆንላችሁ ፣
፳፮ አትብላው ። ነገር ፡ ግን ፡ የተቀደሰውን ፡ ነገር
ህን ፡ ስእለትህንም ፡ ይዘህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡
፳፯ መረጠው ፡ ስፍራ ፡ ሂድ ። የሚቃጠለውንም ፡
መሥዋዕትህን ፣ ሥጋውንና ፡ ደሙን ፣ በአምላ
ክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ አቅርብ ፤
የመሥዋዕትህም ፡ ደም ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ ይፍሰስ ፣ ሥጋው
፳፰ ንም ፡ ብላው ። በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ መልካምና ፡ ቅን ፡ የሆነውን ፡ ነገር ፡ ስታ
ደርግ ፡ ለአንተ ፡ ከአንተም ፡ በኋላ ፡ ለልጆችህ ፡
ለዘላለም ፡ መልካም ፡ ይሆንላችሁ ፡ ዘንድ ፡ እኔ ፡
የማዝዝህን ፡ እነዚህን ፡ ቃሎች ፡ ሁሉ ፡ ሰምተህ ፡
ጠብቅ ።

፳፱ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትወርሳቸው ፡
ዘንድ ፡ የምትሄድባቸውን ፡ አሕዛብን ፡ በፊትህ ፡
በጠፉ ፡ ጊዜ ፣ አንተም ፡ በወረስሃቸው ፡ ጊዜ ፣
፴ በምድራቸውም ፡ በተቀመጥህ ፡ ጊዜ ፣ ከፊትህ ፡
ከጠፉ ፡ በኋላ ፡ እነርሱን ፡ ለመከተል ፡ እንዳት
ጠመድ ፡— እነዚህስ ፡ አሕዛብ ፡ አማልክቶቻቸ
ውን ፡ ያመለኩት ፡ እንዴት ፡ ነው ? እንዲሁ ፡
ደግሞ ፡ እኔ ፡ አደርጋለሁ ፡ ብለህ ፡ ስለ ፡ አማል
፴፩ ክቶቻቸው ፡ እንዳትጠይቅ ፡ ተጠንቀቅ ። እግ
ዚአብሔር ፡ የሚጠላውን ፡ ርኵሰት ፡ ሁሉ ፡ እነ
ርሱ ፡ ለአማልክቶቻቸው ፡ አድርገዋልና ፣ ወን
ዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ ደግሞ ፡ ለአማ
ልክቶቻቸው ፡ በእሳት ፡ ያቃጥሉአቸዋልና ፡
አንተ ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እንዲሁ ፡
አታድርግ ።

፴፪ እኔ ፡ የማዝዝህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ታደርገው ፡
ዘንድ ፡ ጠብቅ ፤ ምንም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ አትጨ
ምር ፣ ከእርሱም ፡ ምንም ፡ አታጕድል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ በመካከልህም ፡ ነቢይ ፡ ወይም ፡ ሕልም ፡
አላሚ ፡ ቢነሣ ፣ ምልክትም ፡ ተአምራትም ፡
፪ ቢሰጥህ ፣ እንደ ፡ ነገረህም ፡ ምልክቱ ፡ ተአም
ራቱም ፡ ቢፈጸም ፣ እርሱም ፡— ሄደን ፡ የማታ

ውቃቸውን ፡ ሌሎች ፡ አማልክት ፡ እንከተል ፡
፫ እናምልካቸውም ፡ ቢልህ ፥ አምላካችሁን ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ በፍጹም ፡ ልባችሁ ፡ በፍጹምም ፡
ነፍሳችሁ ፡ ትወድዱት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያውቅ ፡
ዘንድ ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሊፈትና
ችሁ ፡ ነውና ፡ የዚያን ፡ ነቢይ ፡ ቃል ፡ ወይም ፡
፬ ያን ፡ ሕልም ፡ አላሚ ፡ አትስማ ። አምላካች
ሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተከተሉ ፥ እርሱንም ፡
ፍሩ ፥ ትእዛዙንም ፡ ጠብቁ ፥ ቃሉንም ፡ ስሙ ፥
እርሱንም ፡ አምልኩ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ተጣ
፭ በቁ ። አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትሄድበት ፡
ዘንድ ፡ ካዘዘህ ፡ መንገድ ፡ ሊያወጣህ ፥ ከግብፅ ፡
ምድር ፡ ካወጣችሁ ፡ ከባርነትም ፡ ቤት ፡ ካዳና
ችሁ ፡ ከአምላካችሁ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ሊያስ
ታችሁ ፡ ተናግሮአልና ፡ ያ ፡ ነቢይ ፡ ወይም ፡
ያ ፡ ሕልም ፡ አላሚ ፡ ይገደል ፤ እንዲሁም ፡ ክፉ
ውን ፡ ነገር ፡ ከመካከልህ ፡ አርቅ ።

፮-፯ የእናትህ ፡ ልጅ ፡ ወንድምህ ፡ ወይም ፡ ወንድ ፡
ልጅህ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ልጅህ ፡ ወይም ፡ በብብ
ትህ ፡ ያለች ፡ ሚስትህ ፡ ወይም ፡ እንደ ፡ ነፍስህ ፡
ያለ ፡ ወዳጅህ ፡ በስውር ፦ና ፥ ሄደን ፡ ከምድር ፡
ዳር ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳር ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡
አንተ ፡ የቀረቡት ፡ ከአንተም ፡ የራቁት ፡ አንተን ፡
ከብበው ፡ ያሉ ፡ አሕዛብ ፡ ከሚያመልኩአቸው ፡
አማልክት ፥ አንተም ፡ አባቶችህም ፡ የማታ
ውቋቸውን ፡ ሌሎች ፡ አማልክት ፡ እናምልክ ፡
፰ ብሎ ፡ ቢያስትህ ፥ እሺ ፡ አትበለው ፥ አትስማ
ውም ፤ ዓይንህም ፡ አይራራለት ፥ አትማረውም ፥
፱ አትሸሽገውም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ፈጽመህ ፡ ግደ
ለው ፤ እርሱን ፡ ለመግደል ፡ በፊት ፡ የአንተ ፡
እጅ ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡
፲ በላዩ ፡ ትሁን ። ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ከባርነት ፡
ቤት ፡ ካወጣህ ፡ ከአምላክህ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ሊያርቅህ ፡ ወድዶአልና ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ በድ
፲፩ ንጋይ ፡ ውገረው ። እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ሰም
ተው ፡ ይፈራሉ ፥ እንዲህም ፡ ያለ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡
እንደ ፡ ገና ፡ በአንተ ፡ መካከል ፡ አያደርጉም ።

፲፪-፲፫ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልትኖርበት ፡ በሚ
ሰጥህ ፡ በአንዲቱ ፡ ከተማህ ፦ ክፉተኞች ፡
ሰዎች ፡ ከእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ወጥተው ፦ ሄደን ፡
የማታውቋቸውን ፡ ሌሎችን ፡ አማልክት ፡ እና
ምልክ ፡ ብለው ፡ የከተማቸውን ፡ ሰዎች ፡ አሳቱ ፡
፲፬ ሲሉ ፡ ወሬ ፡ ብትሰማ ፥ ትፈልጋለህ ፥ ትመረ
ምራለህም ፥ ትጠይቃለህም ፤ እነሆም ፥ እው
ነት ፡ ቢሆን ፥ ይህም ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ በመካከልህ ፡
፲፭ እንደ ፡ ተደረገ ፡ እርግጥ ፡ ሆኖ ፡ ቢገኝ ፥ የዚያ
ችን ፡ ከተማ ፡ ሰዎች ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ ፈጽሞ ፡
ትመታቸዋለህ ፤ ከተማይቱን ፥ በእርስዋም ፡
ያለውን ፡ ሁሉ ፥ እንስሳውንም ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡
፲፮ ታጠፋቸዋለህ ። ዕቃዋንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ አደ
ባባይዋ ፡ ትሰበስባለህ ፥ ከተማይቱንም ፡ ዕቃ
ዋንም ፡ ሁሉ ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
በእሳት ፡ ፈጽመህ ፡ ታቃጥላለህ ፤ ለዘላለምም ፡
ወና ፡ ትሆናለች ፥ ደግሞም ፡ አትሠራም ።
፲፯-፲፰ ዛሬም ፡ እኔ ፡ የማዝዝህን ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ትጠ
ብቅ ፡ ዘንድ ፥ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡
የአምላክህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስት
ሰማ ፥ የእግዚአብሔር ፡ መቅሠፍት ፡ ቍጣ ፡
ይመለስ ፡ ዘንድ ፥ ለአባቶችህም ፡ እንደ ፡ ማለ
ላቸው ፡ ይምርህ ፡ ዘንድ ፥ ይራራልህም ፡ ዘንድ ፥
ያበዛህም ፡ ዘንድ ፥ እርም ፡ ከሆነው ፡ አንዳች ፡
ነገር ፡ በእጅህ ፡ አይንጠልጠልብህ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩-፪ እናንተ ፡ የአምላካችሁ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ልጆች ፡ ናችሁ ፤ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
አንተ ፡ ቅዱስ ፡ ሕዝብ ፡ ነህና ፥ በምድርም ፡
ላይ ፡ ከሚኖሩ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ለእ
ርሱ ፡ ለራሱ ፡ ሕዝብ ፡ ትሆንለት ፡ ዘንድ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ አንተን ፡ መርጦአልና ፡ ስለ ፡ ሞተው ፡
ሰው ፡ አካላችሁን ፡ አትንጩ ፥ በዓይኖቻችሁም ፡
መካከል ፡ ራሳችሁን ፡ አትላጩ ።

፫-፬ ርኩስን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አትብላ ። የምትበሉ
አቸው ፡ እንስሶች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ በሬ ፥
፭ በግ ፥ ፍየል ፥ ዋላ ፥ ሚዳቋ ፥ የበረሃ ፡ ፍየል ፥
፮ አጋዘን ፥ አጭ ፥ በራይሌ ፥ ድኩላ ። ከእንስ
ሶች ፡ ሰኰናው ፡ የተሰነጠቀውን ፥ ጥፍሩም ፡
ከሁለት ፡ የተከፈለውን ፥ የሚያመሰኳውንም ፡
፯ እንስሳ ፡ ሁሉ ፡ ትበላላህ ። ነገር ፡ ግን ፡ ከሚያ
መስኩ ፡ ወይም ፡ ሰኰናቸው ፡ ከተሰነጠቀ ፡ እነ
ዚህን ፡ አትበሉም ፤ ግመልን ፥ ጥንቸልን ፥
ሽኮኮን ፡ አትበሉም ። ያመሰኳሉና ፥ ነገር ፡
ግን ፡ ሰኰናቸው ፡ አልተሰነጠቀምና ፡ እነዚህ ፡
፰ ለእናንተ ፡ ርኩሶች ፡ ናቸው ። እርያም ፥ ሰኰ
ናው ፡ ስለ ፡ ተሰነጠቀ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ስላላመሰኳ ፥
እርሱ ፡ ለእናንተ ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤ ሥጋውን ፡
አትብሉ ፥ በድኑንም ፡ አትንኩ ።

፱ በውኆች ፡ ውስጥ ፡ ከሚኖሩት ፡ ሁሉ ፡ የም
ትበሉአቸው ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ክንፍና ፡ ቅር
፲ ፊት ፡ ያላቸውን ፡ ትበላላችሁ ። ክንፍና ፡ ቅር
ፊትም ፡ የሌላቸውን ፡ አትበሉም ፤ ለእናንተ ፡
ርኩስ ፡ ናቸው ።

፲፩ ንጹሕ ፡ የሆኑትን ፡ ወፎች ፡ ሁሉ ፡ ብሉ ።
፲፪ ሊበሉ ፡ የማይገባቸው ፡ ግን ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤
፲፫ ንስር ፥ ገዴ ፥ ዓሣ ፡ አውጭ ፥ ጭልፊት ፥ ጭላት ፡
፲፬-፲፭ በየወገኑ ፥ ቍራም ፡ ሁሉ ፡ በየወገኑ ፥ ሰጐን ፥
፲፮ ጠላቋ ፥ ዝዩ ፥ በቋል ፡ በየወገኑ ፥ ጕጕት ፥
፲፯ ጋጋኖ ፥ የውኃ ፡ ዶሮ ፥ ይብራ ፥ ጥምብ ፡ አንሣ ፡
፲፰ አሞራ ፥ እርኩም ፥ ሽመላ ፥ ሳቢሳ ፡ በየወገኑ ፥
፲፱ ጅንጅላቲ ፡ ወፍ ፥ የሌሊት ፡ ወፍ ። የሚበርርም ፡
ተንቀሳቃሽ ፡ ሁሉ ፡ ለእናንተ ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤
፳ አይበላም ። ንጹሕ ፡ የሆኑትን ፡ ወፎች ፡ ሁሉ ፡
ብሉ ።

፳፩ አንተ ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተ
ቀደሰ ፡ ሕዝብ ፡ ነህና ፡ የበከተውን ፡ ሁሉ ፡ አት
ብላ ፤ ይበላው ፡ ዘንድ ፡ በአገርህ ፡ ደጅ ፡ ለተቀ
መጠ ፡ መጻተኛ ፡ ትሰጠዋለህ ፥ ወይም ፡ ለእን

ግዳ ፡ ትሸጠዋለህ ። የፍየሉን ፡ ጠቦት ፡ በእናቱ ፡
ወተት ፡ አትቀቅል ።

፳፪፡ ከእርሻህ ፡ በየዓመቱ ፡ ከምታገኘው ፡ ከዘርህ ፡
፳፫፡ ፍሬ ፡ ሁሉ ፡ አሥራት ፡ ታወጣለህ ። ሁልጊዜ ፡
አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ትማር ፡
ዘንድ ፥ ስሙ ፡ እንዲጠራበት ፡ በመረጠው ፡
ስፍራ ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
የእህልህን ፡ የወይን ፡ ጠጅህንም ፡ የዘይትህንም ፡
አሥራት ፡ የላምህንና ፡ የበግህንም ፡ በኵራት ፡
፳፬፡ ብላ ። አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በባረከህ ፡
ጊዜ ፥ መንገዱ ፡ሩቅ ፡ ቢሆን ፥ አምላክህም ፡
እግዚአብሔር ፡ ስሙን ፡ ያኖርበት ፡ ዘንድ ፡ የመ
ረጠው ፡ ስፍራ ፡ ቢርቅብህ ፥ ይህን ፡ ወደዚያ ፡
፳፭፡ ለመሸከም ፡ ባትችል ፥ ትሸጠዋለህ ፥ የዋጋው
ንም ፡ ገንዘብ ፡ በእጅህ ፡ ይዘህ ፡ አምላክህ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ወደ ፡ መረጠው ፡ ስፍራ ፡ ትሄዳ
፳፮፡ ለህ ። በዚያም ፡ በገንዘቡ ፡ ሰውነትህ ፡ የፈለገ
ውን ፥ በሬ ፡ ወይም ፡ በግ ፡ ወይም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡
ወይም ፡ ብርቱ ፡ መጠጥ ፡ ሰውነትህም ፡ የሚ
ሻውን ፡ ሁሉ ፡ ትገዛለህ ፤ በዚያም ፡ በአምላ
ክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ትበላዋለህ ፥ አን
፳፯፡ ተና ፡ ቤተ ፡ ሰብህም ፡ ደስ ፡ ይላችኋል ። ድር
ሻና ፡ ርስት ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ስለሌለው ፡ በአገ
ርህ ፡ ደጅ ፡ ውስጥ ፡ ያለውን ፡ ሌዋዊ ፡ ቸል ፡
አትበል ።

፳፰፡ በየሦስተኛው ፡ ዓመት ፡ መጨረሻ ፡ በዚያ ፡
ዓመት ፡ የፍሬህን ፡ አሥራት ፡ ሁሉ ፡ አምጥተህ ፡
፳፱፡ በአገርህ ፡ ደጅ ፡ ውስጥ ፡ ታኖረዋለህ ፤ ሌዋዊ
ውም ፥ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ክፍልና ፡ ርስት ፡ የለው
ምና ፥ በአገርህም ፡ ደጅ ፡ ያለ ፡ መጻተኛ ፡ ድሀ ፡
አደግም ፡ መበለትም ፡ መጥተው ፡ ይበላሉ ፡ ይጠ
ግባሉም ፤ ይኸውም ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በምታደርገው ፡ በእጅህ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡
ይባርክህ ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩፡ በየሰባቱ ፡ ዓመት ፡ መጨረሻ ፡ የዕዳ ፡ ምሕረት ፡
፪፡ ታደርጋለህ ። ለምሕረቱም ፡ የሚገባ ፡ ወግ ፡
ይህ ፡ ነው ፤ አበዳሪ ፡ ሁሉ ፡ ለባልንጀራው ፡
ያበደረውን ፡ ይተዋል ፤ የእግዚአብሔር ፡ ይቅ
ርታ ፡ ታውጆአልና ፡ ያበደረውን ፡ ከባልንጀ
፫፡ ራው ፡ ወይም ፡ ከወንድሙ ፡ አይሻ ። ከእን
ግዳ ፡ ላይ ፡ ያበደርኸውን ፡ መፈለግ ፡ ትችላ
ለህ ፤ በወንድምህ ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡
፬፡፭፡ እጅህ ፡ ይተወዋል ። አምላክህም ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ትወርሳት ፡ ዘንድ ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ በሰ
ጠህ ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእውነት ፡
ይባርክሃልና ፡ አንተ ፡ የአምላክህን ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ቃል ፡ ፈጽመህ ፡ ብትሰማ ፥ ታደርጋ
ትም ፡ ዘንድ ፡ ዛሬ ፡ የማዝዝህን ፡ ይህችን ፡ ትእ
ዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ብትጠብቅ ፥ በመካከልህ ፡ ድሀ ፡
፮፡ አይኖርም ። አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡
ተስፋ ፡ እንደ ፡ ሰጠህ ፡ ይባርክሃል ፤ ለብዙ ፡
አሕዛብም ፡ ታበድራለህ ፥ አንተ ፡ ግን ፡ አትበ
ደርም ፤ ብዙ ፡ አሕዛብንም ፡ ትገዛለህ ፥ አንተን ፡
ግን ፡ አይገዙህም ።

፯፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሰጠህ ፡ በአገ
ርህ ፡ ደጅ ፡ ውስጥ ፡ ከሚኖሩ ፡ ከወንድሞችህ ፡
አንዱ ፡ ቢደኸይ ፥ ልብህን ፡ አታጽና ፥ በድ
ሀው ፡ ወንድምህ ፡ ላይ ፡ እጅህን ፡ አትጨብጥ ።
፰፡ ነገር ፡ ግን ፡ እጅህን ፡ ለእርሱ ፡ ክፈት ፥ የለመነ
፱፡ ህንም ፡ አስፈላጊውን ፡ ነገር ፡ አበድረው ። ሰባ
ተኛው ፡ ዓመት ፡ የዕዳ ፡ ምሕረት ፡ ዓመት ፡ ቀር
በአል ፡ ብለህ ፡ ክፉ ፡ አሳብ ፡ በልብህ ፡ እንዳታ
ስብ ፥ ለድሀውም ፡ ወንድምህ ፡ እንዳች ፡ የማት
ሰጥ ፡ እንዳትሆን ፥ ዓይንህም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡
ክፉ ፡ እንዳይሆን ፥ እርሱም ፡ ወደ ፡ እግዚአ
ብሔር ፤ በአንተ ፡ ላይ ፡ እንዳይጮኽ ፥ ኃጢአ
፲፡ ትም ፡ እንዳይሆንብህ ፡ ተጠንቀቅ ። እጅህን ፡
በምትጥልበት ፡ ሁሉ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ስለዚህ ፡ በሥራህ ፡ ሁሉ ፡ ይባርክሃልና ፡
ፈጽመህ ፡ስጠው ፥ በሰጠኸውም ፡ ጊዜ ፡ በል
፲፩፡ ብህ ፡ አትጸጸት ። ድሆች ፡ ከምድሪቱ ፡ ላይ ፡
አያልቁምና ፡ ስለዚህ ፡ እኔ ፡ — በአገርህ ፡ ውስጥ ፡
ላለው ፡ ድሀ ፡ ለተቸገረውም ፡ ወንድምህ ፡ እጅ
ህን ፡ ትከፍታለህ ፡ ብዬ ፡ አዝዝሃለሁ ።

፲፪፡ አንተም ፡ ወንድምህን ፡ ዕብራዊውን ፡ ወይም ፡
ዕብራዊቱን ፡ ብትገዛ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ያገል
ግሉህ ፤ በሰባተኛውም ፡ ዓመት ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡
፲፫፡ አርነት ፡ አውጣው ። ከአንተም ፡ ዘንድ ፡ አርነት ፡
፲፬፡ ባወጣኸው ፡ ጊዜ ፡ባዶውን ፡ አትስደደው ፤ ነገር ፡
ግን ፡ ከመንጋህ ፥ ከአውድማህም ፥ ከወይንህም ፡
መጥመቂያ ፡ ትለግስለታለህ ፤ አምላክህ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንደ ፡ ባረከህ ፡ መጠን ፡ ትሰጠዋለህ ።
፲፭፡ አንተም ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ ባሪያ ፡ እንደ ፡ ነበ
ርህ ፡ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዳነህ ፡
አስብ ፤ ስለዚህ ፡ እኔ ፡ ዛሬ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ አዝ
፲፮፡ ዝሃለሁ ። እርሱ ፡ ግን ፡ አንተንና ፡ ቤትህን ፡
ስለ ፡ ወደደ ፥ ከአንተም ፡ ጋር ፡ መልካም ፡ ስለ ፡
፲፯፡ ሆነለት ፡ — ልወጣ ፡ አልወድድም ፡ ቢል ፥ አንተ ፡
ወስፌ ፡ ወስደህ ፡ በቤትህ ፡ በር ፡ ላይ ፡ ጆሮውን ፡
ትበሳዋለህ ፥ ለዘላለምም ፡ ባሪያ ፡ ይሆንልሃል ።
በሴት ፡ ባሪያህ ፡ ደግሞ ፡ እንዲሁ ፡ ታደርጋለህ ።
፲፰፡ እርሱንም ፡ አርነት ፡ ባወጣኸው ፡ ጊዜ ፡ የምን
ደኛነቱን ፡ ሥራ ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ አድርጎ ፡ ስድ
ስት ፡ ዓመት ፡ አገልግሎሃልና ፡ አይክበድህ ፤
አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ በምትሠራው ፡
ሁሉ ፡ ይባርክሃል ።

፲፱፡ ላምህና ፡ በግህ ፡ የወለዱትን ፡ ተባት ፡ የሆነ
ውን ፡ በኵራት ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ትቀድሳለህ ፤ በበሬህ ፡ በኵራት ፡ አትሥራበት ፥
፳፡ የበግህንም ፡ በኵራት ፡ አትሸልት ። አምላክህ ፡
እግዚአብሔር ፡ በመረጠው ፡ ስፍራ ፡ አንተና ፡
ቤተ ፡ሰብህ ፡ በየዓመቱ ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብ
፳፩፡ ሔር ፡ ፊት ፡ ብሉአቸው ። ነውረኛ ፡ ወይም ፡ አን
ካሳ ፡ ወይም ፡ ዕውር ፡ ቢሆን ፥ ወይም ፡ እንዳች ፡
ክፉ ፡ ነውር ፡ ቢኖረው ፥ ለአምላክህ ፡ ለእግዚ
፳፪፡ አብሔር ፡ አትሠዋው ። በአገርህ ፡ ደጅ ፡ ውስጥ ፡

ትበላዋለህ ፤ ንጹሕ ፡ ሰው ፡ ንጹሕም ፡ ያልሆነ ፡ ሚዳቋና ፡ ዋላ ፡ እንደሚበሉ ፡ ይበሉታል ።
፳፫ ነገር ፡ ግን ፡ ደሙን ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አፍስሰው ፡ እንጂ ፡ አትብላው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ በአቢብ ፡ ወር ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሌሊት ፡ ከግብፅ ፡ ስላወጣህ ፡ የአቢብን ፡ ወር ፡ ጠብቅ ፥ የአምላክህንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡
፪ ፋሲካ ፡ አድርግበት ። አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚያ ፡ ስሙ ፡ ይጠራበት ፡ ዘንድ ፡ በመረጠው ፡ ስፍራ ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ከበግና ፡
፫ ከላም ፡ መንጋ ፡ ፋሲካ ፡ ሠዋ ። የቦካውን ፡ እንጀራ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አትብላ ፤ ከግብፅ ፡ አገር ፡ በችኰላ ፡ ስለ ፡ ወጣህ ፡ ከግብፅ ፡ አገር ፡ የወጣህበትን ፡ ቀን ፡ በዕድሜህ ፡ ሁሉ ፡ ታስብ ፡ ዘንድ ፡ የመከራን ፡ እንጀራ ፥ ቂጣ ፡ እንጀራ ፥ ሰባት ፡
፬ ቀን ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ብላ ። ሰባት ፡ ቀንም ፡ በአገርህ ፡ ሁሉ ፡ እርሾ ፡ አይታይም ፤ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ማታ ፡ ከሠዋኸው ፡ ሥጋ ፡ እስከ ፡
፭ ነገ ፡ ድረስ ፡ ምንም ፡ አይደር ። አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሰጠህ ፡ ከአገርህ ፡ ደጆች ፡ በማንኛይቱም ፡ ፋሲካን ፡ ትሠዋ ፡ ዘንድ ፡ አይገባህም ።
፮ ነገር ፡ ግን ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስሙ ፡ ይጠራበት ፡ ዘንድ ፡ በመረጠው ፡ በዚያ ፡ ስፍራ ፡ ከግብፅ ፡ በወጣህበት ፡ ወራት ፥ ፀሐይ ፡ ሲገባ ፥
፯ ማታ ፡ ፋሲካን ፡ ሠዋ ። አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመረጠው ፡ ስፍራ ፡ ታበስለዋለህ ፥ ትበላውማለህ ፤ በነጋውም ፡ ተነሥተህ ፡ ወደ ፡ ድን
፰ ኳንህ ፡ ትሄዳለህ ። ስድስት ፡ ቀን ፡ ቂጣ ፡ እንጀራ ፡ ብላ ፤ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጉባኤ ፡ ይሁን ፤ ሥራን ፡ ሁሉ ፡ አታድርግበት ።
፱ ሰባት ፡ ሳምንትም ፡ትቈጥራለህ ፤ መከሩን ፡ ማጨድ ፡ ከምትጀምርበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ ሰባት ፡
፲ ሳምንት ፡ መቍጠር ፡ ትጀምራለህ ። አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በባረከህ ፡ መጠን ፡ በፈቃድህ ፡ የምታቀርበውን ፡ አምጥተህ ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሰባቱ ፡ ሱባዔ ፡ በዓል ፡ ታደር
፲፩ ጋለህ ። አንተ ፥ ወንድ ፡ ልጅህና ፡ ሴት ፡ ልጅህ ፥ ወንድ ፡ ባሪያህና ፡ ሴት ፡ ባሪያህ ፥ በአገርህም ፡ ደጅ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፡ ሌዋዊ ፥ በመካከልህም ፡ ያሉት ፡ መጻተኛና ፡ ድሀ ፡ አደግ ፡ መበለትም ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚያ ፡ ስሙ ፡ ይጠራበት ፡ ዘንድ ፡ በሚመርጠው ፡ ስፍራ ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ።
፲፪ አንተም ፡ በግብፅ ፡ ባሪያ ፡ እንደ ፡ ነበርህ ፡ አስብ ፤ ይህንንም ፡ ሥርዓት ፡ ጠብቅ ፥ አድርገውም ።
፲፫ ከአውድማህና ፡ ከመጥመቂያህ ፡ ፍሬህን ፡ በሰበሰብህ ፡ ጊዜ ፡ የዳስ ፡ በዓል ፡ ሰባትን ፡ ቀን ፡
፲፬ ትጠብቃለህ ። አንተም ፥ ወንድ ፡ ልጅህና ፡ ሴት ፡ ልጅህ ፥ ወንድ ፡ ባሪያህና ፡ ሴት ፡ ባሪያህ ፥ በአገርህም ፡ ደጅ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ ሌዋዊና ፡ መጻተኛ ፥ ድሀ ፡ አደግና ፡ መበለትም ፡ በበዓል ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ።
፲፭ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በፍሬህ ፡ ሁሉ ፡ በእጅህም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ይባርክሃልና ፡ እግዚአብሔር ፡ በመረጠው ፡ ስፍራ ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ ታደርጋለህ ፤ አንተም ፡ ፈጽሞ ፡ ደስ ፡
፲፮ ይልሃል ። በዓመት ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፥ በቂጣ ፡ በዓል ፥ በሰባቱ ፡ ሱባዔም ፡ በዓል ፥ በዳስም ፡ በዓል ፡ ወንዶችህ ፡ ሁሉ ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እርሱ ፡ በመረጠው ፡ ስፍራ ፡ ይታዩ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ባዶ ፡ እጃ
፲፯ ቸውን ፡ አይታዩ ። አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በረከት ፡ እንደ ፡ ሰጠህ ፡ መጠን ፡ እያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ችሎታው ፡ ይስጥ ።
፲፰ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሚሰጥህ ፡ በአገርህ ፡ ደጅ ፡ ሁሉ ፡ በየነገዶችህ ፡ ፈራጆችንና ፡ አለቆችን ፡ ሹም ፤ ለሕዝቡም ፡ ቅን ፡ ፍርድ ፡
፲፱ ይፍረዱ ። ፍርድን ፡ አታጣምም ፤ ፊት ፡ አይተህም ፡ አታድላ ፤ ጉቦ ፡ የጥበበኞችን ፡ ዓይን ፡ ያሳውራልና ፥ የጻድቃንንም ፡ ቃል ፡ ያጣምማልና ፡ ጉቦ ፡ አትቀበል ።
፳ በሕይወት ፡ ትኖር ፡ ዘንድ ፥ አምላክህ ፡ እግዚአብሔርም ፡ የሚሰጥህን ፡ ምድር ፡ ትወርስ ፡ ዘንድ ፡ እውነተኛውን ፡ ፍርድ ፡ ተከተል ።
፳፩ ለአንተ ፡ በምትሠራው ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ አጠገብ ፡ ከማናቸውም ፡ ዛፍ ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀድ ፡ አድርገህ ፡ አትትከል ።
፳፪ አምላክህ ፡ እግዚአብሔርም ፡ የሚጠላውን ፡ ሐውልት ፡ ለአንተ ፡ አታቁም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የተጠላ ፡ ነውና ፡ ነውር ፡ ወይም ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ያለበትን ፡ በሬ ፡ ወይም ፡ በግ ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አትሠዋ ።
፪ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሰጠህ ፡ ከአገርህ ፡ ደጆች ፡ በማንኛይቱም ፡ ውስጥ ፡ ወንድ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ቢሆን ፡ ቃል ፡ ኪዳኑን ፡ በማፍረስ ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፋት ፡ የሠራ ፡
፫ ቢገኝ ፥ ሄዶም ፡ ሌሎች ፡ አማልክትን ፡ ያመለከ ፥ እኔ ፡ ላላዘዝኋቸው ፡ ለፀሐይና ፡ ለጨረቃ ፡ ለሰማይም ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ የሰገደ ፡ ቢገኝ ፥
፬ ቢያወሩልህም ፡ ብትሰማም ፥ ያንን ፡ ፈጽመህ ፡ መርምር ፤ እነሆም ፥ እውነት ፡ ቢሆን ፥ በእስራኤልም ፡ መካከል ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ርኵሰት ፡
፭ እንደ ፡ ተሠራ ፡ እርግጥ ፡ ሆኖ ፡ ቢገኝ ፥ ይህን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ የሠሩትን ፡ ያን ፡ ወንድ ፡ ወይም ፡ ያችን ፡ ሴት ፡ ወደ ፡ በርህ ፡ ታመጣቸዋለህ ፥ እስኪሞቱም ፡ ድረስ ፡ በድንጋይ ፡ ትወግራቸ
፮ ዋለህ ። በሁለት ፡ ወይም ፡ በሦስት ፡ ምስክሮች ፡ አፍ ፡ ሞት ፡ የሚገባው ፡ ይገደል ፤ በአ
፯ ንድ ፡ ምስክር ፡ አፍ ፡ አይገደል ። እርሱን ፡ ለመግደል ፡ በመጀመሪያ ፡ የምስክሮች ፡ እጅ ፡ በኋላም ፡ የሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ ትሁንበት ፤ እንዲሁም ፡ ክፉቱን ፡ ከመካከልህ ፡ አስወግድ ።

፰ በደምና ፡ በደም ፥ በፍርድና ፡ በፍርድ ፥
በመቍሰልና ፡ በመቍሰል ፡ መካከል ፡ በአገርህ ፡
ደጅ ፡ ውስጥ ፡ ሰዎች ፡ ስለሚከራከሩበት ፡ ክር
ክር ፡ የሚሳንህ ፡ የፍርድ ፡ ነገር ፡ ቢኖሃ ፥ አንተ ፡
ተነሥተህ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡
፱ መረጠው ፡ ስፍራ ፡ ትወጣለህ ፤ ወደ ፡ ሌዋው
ያን ፡ ካህናት ፡ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ወደ ፡ ተሾ
መው ፡ ፈራጅ ፡ መጥተህ ፡ ትጠይቃለህ ፤ እነር
፲ ሱም ፡ የፍርዱን ፡ ነገር ፡ ይነግሩሃል ። እግዚአብ
ሔር ፡ በመረጠው ፡ ስፍራ ፡ የነገሩህን ፡ የፍርድ ፡
ነገር ፡ ታደርጋለህ ፤ እንዳስተማሩህም ፡ ታደ
፲፩ ርግ ፡ ዘንድ ፡ ጠብቅ ። እንዳስተማሩህም ፡ ሕግ ፥
እንደ ፡ ነገሩህም ፡ ፍርድ ፡ አድርግ ፤ ከነገ
ሩህ ፡ ፍርድ ፡ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡
፲፪ አትበል ። ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ቢኰራ ፥ በዚ
ያም ፡ አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለማገል
ገል ፡ የሚቆመውን ፡ ካህኑን ፡ ወይም ፡ ፈራጁን ፡
ለመስማት ፡ ባይወድድ ፥ ያ ፡ ሰው ፡ ይሙት ፥
ከእስራኤልም ፡ ዘንድ ፡ ክፉትን ፡ አስወግድ ፤
፲፫ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ሰምቶ ፡ ይፈራል ፥ ከዚያም ፡
ወዲያ ፡ አይኰራም ።

፲፬ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደሚሰጥህ ፡
ምድር ፡ በገባህ ፥ በወረስሃትም ፡ ጊዜ ፥ በተቀ
መጥህባትም ፡ ጊዜ ፡— በዙሪያዬ ፡ እንዳሉት ፡
አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ በላዬ ፡ ንጉሥ ፡ አነግሣለሁ ፡
፲፭ ስትል ፥ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ የመረጠ
ውን ፡ በላይህ ፡ ታነግሣለህ ፤ ከወንድሞችህ ፡
መካከል ፡ የሆነውን ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡
ታነግሣለህ ፤ ወንድምህ ፡ ያልሆነውን ፡ ከሌላ ፡
ወገን ፡ ሰው ፡ በላይህ ፡ ንጉሥ ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡
፲፮ አይገባህም ። ነገር ፡ ግን ፡ ለእርሱ ፡ ፈረሶችን ፡
አያበዛም ፤ እግዚአብሔር ፡— በዚያ ፡ መንገድ ፡
ደግማችሁ ፡ አትመለሱም ፡ ብሎአችኋልና ፡
ፈረሶችን ፡ ለማብዛት ፡ ሕዝቡን ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡
፲፯ አይመልስም ። ልቡም ፡ እንዳይስት ፡ ሚስቶ
ችን ፡ ለእርሱ ፡ አያበዛም ፤ ወርቅና ፡ ብርም ፡
ለእርሱ ፡ እጅግ ፡ አያበዛም ።

፲፰ በመንግሥቱም ፡ ዙፋን ፡ በተቀመጠ ፡ ጊዜ ፡
ከሌዋውያን ፡ ካህናት ፡ ወስዶ ፡ ይህን ፡ ሕግ ፡
፲፱፡፳ ለራሱ ፡ በመጽሐፍ ፡ ይጻፍ ። አምላኩን ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ መፍራት ፡ ይማር ፡ ዘንድ ፥ የዚህን ፡
ሕግ ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ይህችንም ፡ ሥርዓት ፡ ጠብቆ ፡
ያደርግ ፡ ዘንድ ፥ ልቡ ፡ በወንድሞቹ ፡ ላይ ፡
እንዳይኰራ ፡ ከትእዛዙም ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ እን
ዳይል ፥ እርሱም ፡ ልጆቹም ፡ በእስራኤል ፡
ልጆች ፡ መካከል ፡ ረጅም ፡ ዘመን ፡ ይነግሡ ፡
ዘንድ ፡ መጽሐፉ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይኑር ፥ ዕድ
ሜውንም ፡ ሁሉ ፡ ያንብበው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ ለሌዋውያን ፡ ካህናት ፥ ለሌዊም ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡
ከእስራኤል ፡ ጋር ፡ ድርሻና ፡ ርስት ፡ አይሆንላ
ቸውም ፤ በእሳት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቀር
በውን ፡ መሥዋዕቱንና ፡ ርስቱን ፡ ይበላሉ ።
፪ በወንድሞቻቸውም ፡ መካከል ፡ ርስት ፡ አይሆ
ንላቸውም ፤ እርሱ ፡ እንደ ፡ ተናገራቸው ፡ ርስ
፫ ታቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ። በሬ ፡ ወይም ፡
በግ ፡ ለመሥዋዕት ፡ ከሚያቀርቡት ፡ ሕዝብ ፡
የካህናቱ ፡ ወግ ፡ ይህ ፡ ይሆናል ፤ ወርቹንና ፡
ሁለቱን ፡ ጕንጮቹን ፡ ጨጓራውንም ፡ ለካህኑ ፡
፬ ይሰጣሉ ። የእህልህን ፡ የወይን ፡ ጠጅህን ፡ የዘ
ይትህንም ፡ በኵራት ፥ አስቀድሞም ፡ የተሸለ
ተውን ፡ የበግህን ፡ ጠጕር ፡ ለእርሱ ፡ ትሰጣለህ ።
፭ እርሱ ፡ ከልጆቹ ፡ ጋር ፡ ተነሥቶ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ስም ፡ ለዘላለም ፡ ያገለግል ፡ ዘንድ ፡ አም
ላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከነገዶችህ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡
መረጠው ፡ ነው ።

፮ አንድ ፡ ሌዋዊ ፡ ሰው ፡ ከሚቀመጥበቸው ፡
በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ ካሉት ፡ ከአገር ፡
ደጆች ፡ ከአንዲቱ ፡ ቢወጣ ፥ በፍጹም ፡ ፈቃ
ድም ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ መረጠው ፡ ስፍራ ፡
፯ ቢመጣ ፥ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንደሚቆ
ሙት ፡ እንደ ፡ ወንድሞቹ ፡ እንደ ፡ ሌዋውያን ፡
ሁሉ ፡ በአምላኩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ያገ
፰ ለግላል ። ከተሸጠው ፡ ከአባቶቹ ፡ ከብት ፡ ዋጋ ፡
ሌላ ፡ እንደ ፡ ባልንጀሮቹ ፡ ከመብል ፡ ድርሻውን ፡
ይወስዳል ።

፱ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደሚሰጥህ ፡
ምድር ፡ በገባህ ፡ ጊዜ ፡ እነዚያ ፡ አሕዛብ ፡ የሚ
ያደርጉትን ፡ ርኵሰት ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ አት
፲ ማር ። ወንድ ፡ ልጁን ፡ ሴት ፡ ልጁን ፡ በእሳት ፡
የሚያሳልፍ ፥ ምዋርተኛም ፥ ሞራ ፡ ገላጭም ፥
፲፩ አስማተኛም ፥ መተተኛም ፥ በድግምት ፡ የሚ
ጠነቍልም ፥ መናፍስትንም ፡ የሚጠራ ፥ ጠን
ቋይም ፥ ሙታን ፡ ሳቢም ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ አይ
፲፪ ገኝ ። ይህንም ፡ የሚያደርግ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ፊት ፡ የተጠላ ፡ ነው ፤ ስለዚህም ፡ ርኵ
ሰት ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከፊትህ ፡ ያሳ
፲፫ ድዳቸዋል ። አንተ ፡ ግን ፡ በአምላክህ ፡ በእግ
፲፬ ዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ፍጹም ፡ ሁን ። የምትወር
ሳቸው ፡ እነዚህ ፡ አሕዛብ ፡ ሞራ ፡ ገላጮችንና ፡
ምዋርተኞችን ፡ ያዳምጣሉ ፤ አንተ ፡ ግን ፡ እን
ዲሁ ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ከልክሎሃል ።

፲፭፡፲፮ አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ በኮሬብ ፡ ስብ
ሰባ ፡ ተደርጎ ፡ በነበረበት ፡ ቀን ፡— እንዳልሞት ፡
የአምላኬን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ድምፅ ፡ደግሞ ፡
አልስማ ፥ ይህችን ፡ ታላቅ ፡ እሳት ፡ ደግሞ ፡
አልይ ፡ ብለህ ፡ እንደ ፡ ለመንኸው ፡ ሁሉ ፥ አም
ላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ መካከል ፡ ከወ
ንድሞችህ ፡ እንደ ፡ እኔ ፡ ያለ ፡ ነቢይ ፡ ያስነሣ
፲፯ ልሃል ፤ እርሱንም ፡ ታደምጣለህ ። እግዚአብ
ሔርም ፡ አለኝ ፡— የተናገሩት ፡ መልካም ፡ ነው ፤
፲፰ ከወንድሞቻቸው ፡ መካከል ፡ እንደ ፡ አንተ ፡
ያለ ፡ ነቢይ ፡ አስነሣላቸዋለሁ ፤ ቃሌንም ፡ በአፉ ፡
አደርጋለሁ ፥ ያዘዝሁትንም ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ይነ
፲፱ ግራቸዋል ፤ በስሜም ፡ የሚናገረውን ፡ ቃሌን ፡
የማይሰማውን ፡ ሰው ፡ እኔ ፡ እበቀልለታለሁ ።

፳፡ ነገር ፡ ግን ፡ ይናገር ፡ ዘንድ ፡ ያላዘዝሁትን ፡
በስሜ ፡ በድፍረት ፡ የሚናገር ፡ ወይም ፡ በሌላ ፡
አማልክት ፡ ስም ፡ የሚናገር ፡ ነቢይ ÷ እርሱ ፡
፳፩፡ ይገደል ። በልብህም ፡— እግዚአብሔር ፡ ያል
ተናገውን ፡ ቃል ፡ እናውቅ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡
፳፪፡ ይቻለናል ? ብትል ÷ ነቢዩ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ስም ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ፡ የተናገረው ፡ ነገር ፡ ባይ
ሆን ፡ ባይመጣም ÷ ያ ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡
ያልተናገረው ፡ ነው ፤ ነቢዩ ፡ በድፍረቱ ፡ ተና
ግሮታል ፡ እርሱን ፡ አትፍራው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምድራቸውን ፡
የሚሰጥህን ፡ አሕዛብ ፡ በጠፉ ፡ ጊዜ ÷ በወረስሃ
ትም ፡ ጊዜ ÷ በከተሞቻቸውና ፡ በቤቶቻቸውም ፡
፪፡ በተቀመጥህ ፡ ጊዜ ÷ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡
ርስት ፡ አድርጎ ፡ በሚሰጥህ ፡ በምድርህ ፡ መካ
ከል ፡ ሦስት ፡ ከተሞችን ፡ ለራስህ ፡ ትለያለህ ።
፫፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ይሸሽባቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እነ
ርሱ ፡ የሚወስደውን ፡ መንገድ ፡ ታዘጋጃለህ ÷
አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚያወርስህን ፡
ምድር ፡ ከሦስት ፡ አድርገህ ፡ ትከፍላለህ ።
፬፡ የነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ወግ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ አስቀድሞ ፡
ጠላቱ ፡ ሳይሆን ፡ ባልንጀራውን ፡ ሳያስብ ፡ የገ
ደለ ፡ ወደዚያ ፡ ሸሽቶ ፡ በሕይወት ፡ ይኑር ።
፭፡፮፡ ሰው ፡ ከባልንጀራው ፡ ጋር ፡ እንጨት ፡ ሊቈ
ርጥ ፡ ወደ ፡ ዱር ፡ ቢሄድ ÷ ዛፉንም ፡ ሊቆርጥ ፡
ምሳሩን ፡ ሲያነሣ ፡ ብረቱ ፡ ከእጀታው ፡ ቢወ
ልቅ ÷ ባልንጀራውንም ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡
ቢመታው ÷ ደም ፡ ተበቃዩ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳዩን ፡
በልቡ ፡ ተናድዶ ፡ እንዳያሳድደው ፡ መንገዱም ፡
ሩቅ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አግኝቶ ፡ እንዳይገድለው ÷ ከእ
ነዚህ ፡ ከተሞች ፡ ወደ ፡ አንዲቱ ፡ ሸሽቶ ፡ በሕ
ይወት ፡ ይኖራል ፤ አስቀድሞ ፡ ጠላቱ ፤ አልነበ
፯፡ ረምና ፡ ሞት ፡ አይገባውም ። ስለዚህ ፡ እኔ ፡—
ለአንተ ፡ ሦስት ፡ ከተሞችን ፡ ለይ ፡ ብዬ ፡ አዝዝ
፰፡ ሃለሁ ። አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአባቶ
ችህ ፡ እንደ ፡ ማለላቸው ፡ ዳርቻህን ፡ ቢያሰፋ ÷
ይሰጣቸውም ፡ ዘንድ ፡ ለአባቶችህ ፡ የተናገረ
፱፡፲፡ ውን ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ቢሰጥህ ÷ አምላክህን ፡
እግዚአብሔርን ፡ ትወድድ ፡ ዘንድ ÷ ሁልጊ
ዜም ፡ በመንገዱ ፡ ትሄድ ፡ ዘንድ ÷ ዛሬ ፡ የማዝ
ዝህን ፡ ይህችን ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ታደርጋት ፡
ዘንድ ፡ ብትጠብቅ ÷ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡
ትወርሳት ፡ ዘንድ ፡ በሚሰጥህ ፡ ምድር ፡ ውስጥ ፡
ንጹሕ ፡ ደም ፡ እንዳይፈስስ ፡ ደምም ፡ በአንተ ፡
ላይ ፡ እንዳይሆን ÷ በእነዚህ ፡ በሦስት ፡ ከተሞች ፡
ላይ ፡ ሌሎች ፡ ሦስት ፡ ከተሞችን ፡ ትጨምራ
ለህ ።
፲፩፡ ሰው ፡ ግን ፡ ባልንጀራውን ፡ ቢጠላ ÷ ቢሸምቅ
በትም ÷ ተነሥቶም ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ ቢመ
ታው ÷ ከእነዚህም ፡ ከተሞች ፡ ወደ ፡ አንዲቱ ፡
፲፪፡ ቢሸሽ ÷ የከተማው ፡ ሽማግሌዎች ፡ ይልካሉ ÷
ከተማጠነበትም ፡ ከተማ ፡ ይነጥቁታል ÷ እንዲ
ሞትም ፡ በደም ፡ ተበቃዩ ፡ እጅ ፡ አሳልፈው ፡
፲፫፡ ይሰጡታል ። ዓይንህ ፡ አትራራለት ፤ ነገር ፡
ግን ፡ መልካም ፡ ይሆንልህ ፡ ዘንድ ፡ ንጹሑን ፡
ደም ፡ ከእስራኤል ፡ ታስወግዳለህ ።
፲፬፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትወርሳት ፡ ዘንድ ፡
በሚሰጥህ ፡ ምድር ፡ በምትወርሳት ፡ ርስትህ ፡
የቀደሙ ፡ ሰዎች ፡ የተከሉትን ፡ የባልንጀራ
ህን ፡ የድንበር ፡ ምልክት ፡ አትንቀል ።
፲፭፡ ስለ ፡ በደል ፡ ሁሉ ÷ ክፉ ፡ በማድረግም ፡ ስለ ፡
ሠራት ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ በማንም ፡ ላይ ፡
አንድ ፡ ምስክር ፡ አይቁም ፤ በሁለት ፡ ምስክ
ሮች ፡ ወይም ፡ በሦስት ፡ ምስክሮች ፡ አፍ ፡
፲፮፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ይጸናል ። በዓመፃ ፡ ይከስሰው ፡
ዘንድ ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ሐሰተኛ ፡ ምስክር ፡
፲፯፡ ቢቆም ÷ ሁለቱ ፡ ጠበኞች ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ በካህናቱና ፡ በዚያ ፡ ዘመን ፡ በሚፈርዱ ፡
፲፰፡ ፈራጆች ፡ ፊት ፡ ይቆማሉ ፤ ፈራጆቹም ፡ አጥ
ብቀው ፡ ይመረምራሉ ፤ ያም ፡ ምስክር ፡ ሐሰ
ተኛ ፡ ምስክር ፡ ሆኖ ፡ በወንድሙ ፡ ላይ ፡ በሐ
፲፱፡ ሰት ፡ ተናግሮ ፡ ቢገኝ ÷ በወንድሙ ፡ ላይ ፡ ያደ
ርገው ፡ ዘንድ ፡ ያሰበውን ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ትመ
ልሱበታላችሁ ፤ እንዲሁም ፡ ከአንተ ፡ መካከል ፡
፳፡ ክፉቱን ፡ ታስወግዳለህ ። የቀሩትም ፡ ሰምተው ፡
ይፈራሉ ÷ እንደዚህ ፡ ያለውንም ፡ ክፉት ፡ ከመ
ካከልህ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ደግሞ ፡ አያደር
፳፩፡ ጉም ። ዓይንህም ፡ አትራራለት ፤ ነፍስ ፡ በነ
ፍስ ÷ ዓይን ፡ በዓይን ÷ ጥርስ ፡ በጥርስ ÷ እጅ ፡
በእጅ ÷ እግር ፡ በእግር ÷ ይመለሳል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩፡ ጠላቶችህን ፡ ለመውጋት ፡ በወጣህ ፡ ጊዜ ÷
ፈረሶችንና ፡ ሰረገሎችን ፡ ሕዝቡንም ፡ ከአንተ ፡
ይልቅ ፡ በዝተው ፡ ባየህ ፡ ጊዜ ÷ ከግብፅ ፡ አገር ፡
ያወጣህ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡
፪፡ ጋር ፡ ነውና ፡ አትፍራቸው ። ወደ ፡ ሰልፍም ፡
በቀረባችሁ ፡ ጊዜ ፡ ካህኑ ፡ ይቅረብ ፡ ለሕዝቡም ፡
፫፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ይንገራቸው ፡— እስራኤል ፡
ሆይ ÷ ስሙ ፤ ዛሬ ፡ ጠላቶቻችሁን ፡ ለመው
ጋት ፡ ትቀርባላችሁ ፤ ልባችሁ ፡ አይታወክ ÷
አትፍሩ ÷ አትንቀጥቀጡ ÷ በፊታቸውም ፡ አት
፬፡ ደንግጡ ፤ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ የሚሄድ ÷ ያድና
ችሁም ፡ ዘንድ ፡ ጠላቶቻችሁን ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡
የሚወጋ ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነውና ።
፭፡ አለቆችም ፡ ለሕዝቡ ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ ይና
ገሩ ፡— አዲስ ፡ ቤት ፡ ሠርቶ ፡ ያላስመረቀ ፡ ሰው ፡
ቢኖር ፡ በሰልፍ ፡ እንዳይሞት ፡ ሌላም ፡ ሰው ፡
እንዳያስመርቀው ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመልሶ ፡ ይሂድ ።
፮፡ ወይንም ፡ ተክሎ ፡ ፍሬውንም ፡ ያልበላ ፡ ሰው ፡
ቢኖር ፡ በሰልፍ ፡ እንዳይሞት ፡ ሌላም ፡ ሰው ፡
ፍሬውን ፡ እንዳይበላ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመልሶ ፡
፯፡ ይሂድ ። ሚስትም ፡ አጭቶ ፡ ያላገባትም ፡ ሰው ፡
ቢኖር ፡ በሰልፍ ፡ እንዳይሞት ፡ ሌላም ፡ ሰው ፡
እንዳያገባት ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመልሶ ፡ ይሂድ ።
፰፡ አለቆቹም ፡ ደግሞ ፡ ጨምረው ፡— ማንም ፡ ፈሪና ፡

ድንጉጥ ፡ ሰው ፡ ቢሆን ፡ እርሱ ፡ ፈርቶ ፡ የወን
ድሞቹን ፡ ልብ ፡ ደግሞ ፡ እንዳያስፈራ ፡ ወደ ፡
ቤቱ ፡ ተመልሶ ፡ ይሂድ ፡ ብለው ፡ ለሕዝቡ ፡ ይና
፱ ገሩ ። አለቆቹም ፡ ለሕዝቡ ፡ ነግረው ፡ በጨረሱ ፡
ጊዜ ፡ በየጭፍራው ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ የጦር ፡
አለቆችን ፡ ይሹሙ ።

፲ ለመዋጋት ፡ ወደ ፡ አንዲት ፡ ከተማ ፡ በደረ
ስህ ፡ ጊዜ ፡ አስቀድመህ ፡ በዕርቅ ፡ ቃል ፡ ጥራ
፲፩ ቸው ። የዕርቅ ፡ ቃልም ፡ ቢመልሱልህ ፡ ደጅም ፡
ቢከፍቱልህ ÷ በከተማ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፡ ሕዝብ ፡
፲፪ ሁሉ ፡ ይገብሩልህ ፡ ያገልግሉህም ። የዕርቅ ፡
ቃልም ፡ ባይመልሱልህ ፡ ከአንተም ፡ ጋር ፡ መዋ
ጋት ፡ ቢወድዱ ÷ አንተ ፡ ከተማይቱን ፡ ትከብ
፲፫ ባለህ ፡ ታስጨንቃትማለህ ፤ አምላክህም ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ በእጅህ ፡ አሳልፎ ፡ በሰጣት ፡ ጊዜ ÷
በእርስዋ ፡ ያሉትን ፡ ወንዶች ፡ ሁሉ ፡ በሰይፍ ፡
፲፬ ስለት ፡ ትገድላቸዋለህ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሴቶቹንና ፡
ሕፃናትን ፡ እንስሶቹንም ፡ በከተማይቱም ፡ ያለ
ውን ፡ ምርኮ ፡ ሁሉ ፡ በዝብዘህ ፡ ለአንተ ፡ ትወ
ስዳለህ ፤ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚ
፲፭ ሰጥህን ፡ የጠላቶችህን ፡ ምርኮ ፡ ትበላለህ ። የእ
ነዚህ ፡ አሕዛብ ፡ ከተሞች ፡ ባይደሉት ፡ ከአንተ ፡
እጅግ ፡ በራቁት ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡
፲፮ ታደርጋለህ ። ነገር ፡ ግን ፡ አምላክህ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ ከሚሰጥህ ፡ ከእነዚህ ፡
አሕዛብ ፡ ከተሞች ፡ ምንም ፡ ነፍስ ፡ አታድንም ።
፲፯፲፰ ነገር ፡ ግን ፡ ለአማልክቶቻቸው ፡ ያደረጉትን ፡
ርኵሰት ፡ ሁሉ ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ እንዳያስተ
ምሩአችሁ ÷ በአምላካችሁም ፡ በእግዚአብሔር ፡
ላይ ፡ ኀጢአት ፡ እንዳትሠሩ ÷ አምላክህ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንዳዘዘህ ፡ ኬጢያዊውን ፡ አሞራዊ
ውንም ፡ ከነዓናዊውንም ፡ ፌርዛዊውንም ፡ ኤዊ
ያዊውንም ፡ ኢያቡሳዊውንም ፡ ፈጽመህ ፡ ታጠ
ፋቸዋለህ ።

፲፱ ከተማይቱን ፡ ለመውሰድ ፡ በመውጋት ፡ ብዙ ፡
ቀን ፡ ከብበህ ፡ ባስጨነቅሃት ፡ ጊዜ ÷ ምሳርህን ፡
አንሥተህ ፡ ዛፎችዋን ፡ አትቍረጥ ፤ ከእነርሱ ፡
ትበላለህና ፡ አትቍረጣቸው ፤ ከብበህ ፡ የምታ
ጠፋው ፡ የምድር ፡ ዛፍ ፡ ሰው ፡ መሆኑ ፡ ነውን ?
፳ ለመብል ፡ የማይሆኑትን ፡ የምታውቃቸውን ፡
ዛፎች ፡ ታጠፋቸዋለህ ÷ ትቈርጣቸውማለህ ፤
እስከታሸንፋትም ፡ ድረስ ፡ በምትዋጋህ ፡ ከተማ ፡
ላይ ፡ ምሽግ ፡ ትመሽጋለህ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትወርሳት ፡ ዘንድ ፡
በሚሰጥህ ፡ ምድር ፡ የተገደለ ፡ ሰው ፡ በሜዳ ፡
፪ ወድቆ ፡ ቢገኝ ÷ ገዳዩም ፡ ባይታወቅ ÷ ሽማግ
ሌዎችህና ፡ ፈራጆችህ ፡ ወጥተው ፡ በተገደለው ፡
ሰው ፡ ዙሪያ ፡ እስካሉት ፡ ከተሞች ፡ ድረስ ፡
፫ በስፍር ፡ ይለኩ ፤ ወደ ፡ ተገደለውም ፡ ሰው ፡ አቅ
ራቢያ ፡ የሆነችው ፡ የከተማይቱ ፡ ሽማግሌዎች ፡
ለሥራ ፡ ያልደረሰችውን ፡ ቀንበርም ፡ ያልተጫነ
፬ ባትን ፡ ጊደር ፡ ይውሰዱ ፤ የዚያችም ፡ ከተማ ፡
ሽማግሌዎች ፡ ጊደሪቱን ፡ ይዘው ፡ ፈሳሽ ፡ ውኃ ፡
ወዳለበት ፡ ወዳልታረሰና ፡ ዘርም ፡ ወዳልተዘራ
በት ፡ ሸለቆ ፡ ይሄዳሉ ፤ በዚያም ፡ በሸለቆው ፡
ውስጥ ፡ የጊደሪቱን ፡ አንገት ፡ ይሰብራሉ ።
፭ የሌዊ ፡ ልጆች ፡ ካህናትም ፡ ይቀርባሉ ፤ በፊቱ ፡
እንዲያገለግሉ ÷ በስሙም ፡ እንዲባርኩ ፡ አም
ላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ መርጦአቸዋልና ÷ በእ
ነርሱም ፡ ቃል ፡ ክርክር ፡ ሁሉ ፡ ጕዳትም ፡ ሁሉ ፡
፮ ይቈረጣልና ፤ ወደ ፡ ተገደለው ፡ ሰው ፡ አቅራ
ቢያ ፡ የሆነችው ፡ የከተማይቱ ፡ ሽማግሌዎች ፡
ሁሉ ፡ በሸለቆው ፡ ውስጥ ፡ አንገትዋ ፡ በተሰበ
ረው ፡ ጊደር ፡ ላይ ፡ እጃቸውን ፡ ሲታጠቡ ፡ —
፯ እጃችን ፡ ይህን ፡ ደም ፡ አላፈሰሰችም ÷ ዓይና
፰ ችንም ፡ አላየችም ፤ አቤቱ ÷ የተቤዠኸውን ፡
ሕዝብህን ፡ እስራኤልን ፡ ይቅር ፡ በል ፤ በሕዝ
ብህም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ የንጹሑን ፡ ደም ፡
በደል ፡ አትቍጠር ፡ ብለው ፡ ይናገራሉ ። ስለ ፡
፱ ደሙም ፡ ይሰረይላቸዋል ። አንተም ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ ዓይን ፡ የቀናውን ፡ ባደረግህ ፡ ጊዜ ፡
የንጹሑን ፡ ደም ፡ በደል ፡ ከመካከልህ ፡ ታርቃ
ለህ ።

፲ ጠላቶችህን ፡ ልትወጋ ፡ በወጣህ ፡ ጊዜ ÷
አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ በእጅህ ፡ አሳልፎ ፡
፲፩ በሰጣቸው ፡ በማረክሃቸውም ፡ ጊዜ ÷ በተማረ
ኩት ፡ መካከል ፡ የተዋበች ፡ ሴት ፡ ብታይ ÷ ብት
መኛትም ፡ ሚስትም ፡ ልታደርጋት ፡ ብትወ
፲፪ ድድ ÷ ወደ ፡ ቤትህ ፡ታመጣታለህ ፤ እርስዋም ፡
ራስዋን ፡ ትላጫለች ÷ ጥፍርዋንም ፡ ትቈርጣ
፲፫ ለች ፤ የተማረከችበትንም ፡ ልብስ ፡ ታወልቃ
ለች ÷ በቤትህም ፡ ተቀምጣ ፡ ስለ ፡ አባትዋና ፡
ስለ ፡ እናትዋ ፡ አንድ ፡ ወር ፡ ሙሉ ፡ ታለቅሳ
ለች ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ትደርስባታለህ ÷ ባልም ፡
ትሆናታለህ ÷ እርስዋም ፡ ሚስት ፡ ትሆንልሃ
፲፬ ለች ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ በእርስዋ ፡ ደስ ፡ ባይ
ልህ ፡ አርነት ፡ አውጥተህ ፡ ወደ ፡ ወደደችው ፡
ትሰድዳታለህ ፤ በዋጋ ፡ ግን ፡ አትሸጣትም ፤ እፍ
ረት ፡ አድርገህባታልና ፡ እንደ ፡ ባሪያ ፡ አትቈ
ጥራትም ።

፲፭ ለአንድ ፡ ሰው ፡ አንዲቱ ፡ የተወደደች ፡ አን
ዲቱም ፡ የተጠላች ፡ ሁለት ፡ ሚስቶች ፡ ቢኖ
ሩት ÷ ለእርሱም ፡ የተወደደችው ፡ ደግሞም ፡
የተጠላችው ፡ ልጆችን ፡ ቢወልዱ ÷ በኵሩም ፡
ከተጠላችው ፡ ሚስት ፡ የተወለደው ፡ ልጅ ፡
፲፮ ቢሆን ÷ ለልጆቹ ፡ ከብቱን ፡ በሚያወርስበት ፡
ቀን ፡ ከተጠላችው ፡ ሚስት ፡ በተወለደው ፡ በበ
ኵሩ ፡ ፊት ፡ ከተወደደችው ፡ ሚስት ፡ የተወለ
ደውን ፡ ልጅ ፡ በኵር ፡ ያደርገው ፡ ዘንድ ፡ አይ
፲፯ ገባውም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከከብቱ ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡
ለእርሱ ፡ በመስጠት ፡ ከተጠላችው ፡ ሚስት ፡
የተወለደው ፡ ልጅ ፡ በኵር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያስ
ታውቅ ። የኃይሉ ፡ መጀመሪያ ፡ ነውና ፡ በኵር
ነቱ ፡ የእርሱ ፡ ነው ።

፲፰ ማንም ፡ ሰው ፡ ለአባቱ ፡ ቃልና ፡ ለእናቱ ፡
ቃል ፡ የማይታዘዝ ፡ ቢቀጡትም ፡ የማይሰማ

ቸው ፡ እልከኛና ፡ ዓመፀኛ ፡ ልጅ ፡ ቢኖረው ፥ ፲፱ አባቱና ፡ እናቱ ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ከተማው ፡ ሽማግሌዎች ፡ ወደሚኖርበትም ፡ ስፍራ ፡ በር ፡ ያምጡት ፤ ፳ የከተማውንም ፡ ሽማግሌዎች ፦ ይህ ፡ ልጃችን ፡ እልከኛና ፡ ዓመፀኛ ፡ ነው ፥ ለቃላችንም ፡ አይታዘዝም ፡ ስስታምና ፡ ሰካራም ፡ ነው ፡ ይበሉአቸው ። ፳፩ የከተማውም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ በድንጋይ ፡ ይውገሩት ፤ እንዲህም ፡ ክፉውን ፡ ነገር ፡ ከመካከልህ ፡ ታርቃለህ ፥ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ሰምተው ፡ ይፈራሉ ።

፳፪ ማንም ፡ ሰው ፡ ለሞት ፡ የሚያበቃውን ፡ ኃጢአት ፡ ቢሠራ ፥ እንዲሞትም ፡ ቢፈረድበት ፥ ፳፫ በእንጨትም ፡ ላይ ፡ ብትሰቅለው ፥ በእንጨት ፡ ላይ ፡ የተሰቀለ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተረገመ ፡ ነውና ፡ ሬሳው ፡ በእንጨት ፡ ላይ ፡ አይደር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ የሰጠህን ፡ ምድር ፡ እንዳታረክስ ፡ በእርግጥ ፡ በዚያው ፡ ቀን ፡ ቅበረው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ የወንድምህ ፡ በሬ ፡ ወይም ፡ በግ ፡ ጠፍቶ ፡ ብታይ ፡ ቸል ፡ አትበል ፤ ወደ ፡ ወንድምህ ፡ መልሰው ። ፪ ወንድምህም ፡ በአቅራቢያህ ፡ ባይሆን ፡ ወይም ፡ ባታውቀው ፡ ይዘህ ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ ትገባለህ ፤ ወንድምህ ፡ እስኪሻው ፡ ድረስ ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ይቀመጣል ፥ ለእርሱም ፡ ትመልሰዋለህ ። ፫ እንዲህም ፡ በአህያው ፡ ወይም ፡ በልብሱ ፡ ታደርጋለህ ፤ እንዲህም ፡ በወንድምህ ፡ በጠፋበት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ባገኘኸው ፡ ጊዜ ፡ ታደርጋለህ ፤ ቸል ፡ ልትለው ፡ አይገባህም ። ፬ የወንድምህ ፡ አህያ ፡ ወይም ፡ በሬው ፡ በመንገድ ፡ ወድቆ ፡ ብታይ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሆነህ ፡ አንሣው ፡ እንጂ ፡ ቸል ፡ አትበለው ።

፭ ሴት ፡ የወንድ ፡ ልብስ ፡ አትልበስ ፥ ወንድም ፡ የሴት ፡ ልብስ ፡ አይልበስ ፤ ይህን ፡ የሚያደርግ ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተጠላ ፡ ነውና ።

፮ በመንገድ ፡ ስትሄድ ፡ በዛፍ ፡ ወይም ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ እናቲቱ ፡ በጫጩቶችዋ ፡ ወይም ፡ በእንቍላሎችዋ ፡ ላይ ፡ ተኝታ ፡ ሳለች ፡ የወፍ ፡ ጎጆ ፡ ብታገኝ ፥ እናቲቱን ፡ ከጫጩቶችዋ ፡ ፯ ጋር ፡ አትውሰድ ። ነገር ፡ ግን ፡ መልካም ፡ ይሆንልህ ፡ ዘንድ ፡ ዕድሜህም ፡ ይረዝም ፡ ዘንድ ፡ እናቲቱን ፡ ስደድ ፥ ጫጩቶችንም ፡ ለአንተ ፡ ውሰድ ።

፰ አዲስ ፡ ቤት ፡ በሠራህ ፡ ጊዜ ፡ ማንም ፡ ከእርሱ ፡ ወድቆ ፡ ደሙን ፡ በቤትህ ፡ ላይ ፡ እንዳታመጣ ፡ በጣራው ፡ ዙሪያ ፡ መከታ ፡ አድርግለት ።

፱ የዘራኸው ፡ ዘርና ፡ ከወይኑ ፡ የወጣው ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡ እንዳይጠፋብህ ፡ በወይንህ ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ ፲ ሁለት ፡ ዓይነት ፡ ዘር ፡ አትዝራ ። በበሬና ፡ በአ ፲፩ ህያ ፡ በአንድነት ፡ አትረስ ። ከተልባ ፡ እግርና ፡ ከበግ ፡ ጠጕር ፡ በአንድነት ፡ የተሠራ ፡ ልብስ ፡ አትልበስ ።

፲፪ በምትለብሰው ፡ በልብስህ ፡ በአራቱ ፡ ማዕዘን ፡ ዘርፍ ፡ አድርግ ።

፲፫ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ሚስት ፡ ቢያገባ ፥ ከደረ ፲፬ ሰባትም ፡ በኋላ ፡ ቢጠላት ፥ የነውር ፡ ነገር ፡ አውርቶ ፦ እኔ ፡ ይህችን ፡ ሴት ፡ ሚስት ፡ አድርጌ ፡ አገባኋት ፥ በደረስሁባትም ፡ ጊዜ ፡ ድንግልናዋን ፡ አላገኘሁባትም ፡ ብሎ ፡ በክፉ ፡ ስም ፡ ፲፭ ቢያሰጣት ፥ የብላቴናይቱ ፡ አባትና ፡ እናት ፡ የድንግልናዋን ፡ ምልክት ፡ ወስደው ፡ በበሩ ፡ አደባባይ ፡ ወደ ፡ ተቀመጡ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ሽማ ፲፮ ግሌዎች ፡ ያምጡት ፤ የብላቴናይቱም ፡ አባት ፡ ሽማግሌዎቹን ፦ እኔ ፡ ለዚህ ፡ ሰው ፡ ልጄን ፡ ፲፯ ዳርሁለት ፡ እርሱም ፡ ጠላት ፤ እነሆም ፦ በልጅህ ፡ ድንግልና ፡ አላገኘሁባትም ፡ ብሎ ፡ የነውር ፡ ነገር ፡ አወራባት ፤ የልጄም ፡ ምልክት ፡ ይኸው ፡ ይላቸዋል ። በከተማም ፡ ሽማግሌ ፲፰ ዎች ፡ ፊት ፡ ልብሱን ፡ ይዘረጋሉ ። የዚያችም ፡ ከተማ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ያንን ፡ ሰው ፡ ወስደው ፡ ፲፱ ይግረፉት ፤ በእስራኤል ፡ ድንግል ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ስም ፡ አምጥቶአልና ፡ መቶ ፡ የብር ፡ ሰቅል ፡ ያስከፍሉት ፥ ለብላቴናይቱም ፡ አባት ፡ ይስጡት ፤ እርስዋም ፡ ሚስት ፡ ትሁነው ፥ በዕድሜውም ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ሊፈታት ፡ አይገባውም ።

፳ ነገሩ ፡ ግን ፡ እውነት ፡ ቢሆን ፥ በብላቴናይ ፳፩ ቱም ፡ ድንግልናዋ ፡ ባይገኝ ፥ ብላቴናይቱን ፡ ወደ ፡ አባትዋ ፡ ቤት ፡ ደጅ ፡ ያውጡአት ፥ በእስራኤልም ፡ ዘንድ ፡ የማይገባውን ፡ ነገር ፡ አድርጋለችና ፥ በአባትዋም ፡ ቤት ፡ አመንዝራለችና ፡ የከተማዋ ፡ ሰዎች ፡ እስክትሞት ፡ ድረስ ፡ በድንጋይ ፡ ይውገሩአት ፤ እንዲሁም ፡ ክፉውን ፡ ነገር ፡ ከመካከልህ ፡ ታስወግዳለህ ።

፳፪ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ከሌላ ፡ ሰው ፡ ሚስት ፡ ጋር ፡ ተኝቶ ፡ ቢገኝ ፥ አመንዝራውና ፡ አመንዝራይቱ ፡ ሁለታቸው ፡ ይሙቱ ፤ እንዲሁም ፡ ክፉውን ፡ ነገር ፡ ከእስራኤል ፡ ታስወግዳለህ ።

፳፫ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ድንግልና ፡ ያላትን ፡ ልጃገረድ ፡ ቢያጭ ፥ ሌላ ፡ ሰውም ፡ በከተማ ፡ ውስጥ ፡ ፳፬ አግኝቶ ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ ቢተኛ ፥ ሁለቱን ፡ ወደ ፡ ዚያች ፡ ከተማ ፡ በር ፡ አውጡአቸው ፤ ብላቴናይቱ ፡ በከተማ ፡ ውስጥ ፡ ሳለች ፡ አልጮኸችምና ፥ ሰውዮውም ፡ የባልንጀራውን ፡ ሚስት ፡ አስነውሮአልና ፡ እስኪሞቱ ፡ ድረስ ፡ በድንጋይ ፡ ውገሩአቸው ፤ እንዲሁም ፡ ክፉውን ፡ ነገር ፡ ከመካከልህ ፡ ታስወግዳለህ ።

፳፭ ነገር ፡ ግን ፡ ሰው ፡ የታጨችውን ፡ ልጃገረድ ፡ በሜዳ ፡ ቢያገኛት ፥ በግድ ፡ አሸንፎም ፡ ቢደርስባት ፥ ያ ፡ የደረሰባት ፡ ሰው ፡ ብቻውን ፡ ይገ ፳፮ ደል ። በብላቴናይቱ ፡ ላይ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ አታድርጉ ፤ በብላቴናይቱ ፡ ላይ ፡ ለሞት ፡ የሚያበቃ ፡ ኃጢአት ፡ የለበትም ፤ ሰው ፡ በባልንጀራው ፡ ላይ ፡ ተነሥቶ ፡ እንደሚገድለው ፡ ይህ ፡ ፳፯ ነገር ፡ ደግሞ ፡ እንደዚሁ ፡ ነውና ፤ በሜዳ ፡ ባገኛት ፡ ጊዜ ፡ የታጨችው ፡ ልጃገረድ ፡ ጮኸለችና ፥ የሚታደጋትም ፡ አልነበረምና ።

፳፰ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ድንግልና ፡ ያላትን ፡ ያል ታጨች ፡ ልጃገረድ ፡ ቢያገኝ ÷ ወስዶም ፡ ቢደር ፳፱ ስባት ÷ ቢያገኙትም ÷ ያ ፡ የደረሰባት ፡ ሰው ፡ አምሳ ፡ የብር ፡ ሰቅል ፡ ለብላቴናይቱ ፡ አባት ፡ ይስጥ ፤ አስነውሮአታልና ፡ ሚስት ፡ ትሁነው ፤ በዕድሜውም ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ሊፈታት ፡ አይገ ባውም ።

፴ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ የአባቱን ፡ ሚስት ፡ አይ ውሰድ ÷ የአባቱንም ፡ ልብስ ፡ ጫፍ ፡ አይግለጥ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ ቍላው ፡ የተቀጠቀጠ ፡ ብልቱም ፡ የተቈ ረጠ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጉባኤ ፡ አይግባ ። ፪ ዲቃላ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጉባኤ ፡ አይ ግባ ፤ እስከ ፡ አሥር ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጉባኤ ፡ አይግባ ።

፫፡፬ ከግብፅ ፡ በወጣችሁ ፡ ጊዜ ፡ እንጀራና ፡ ውኃ ፡ ይዘው ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ አልተቀበሉአችሁ ምና ÷ በመስጴጦምያ ፡ ከለው ፡ ከፋቱራ ፡ የቢ ዖርን ፡ ልጅ ፡ በለዓምን ፡ ዋጋ ፡ ሰጥተው ፡ ይረግ ምህ ፡ ዘንድ ፡ አምጥተውብሃልና ፡ አሞናዊና ፡ ሞዓባዊ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጉባኤ ፡ አይ ግባ ፡ እስከ ፡ አሥር ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ ለዘላ ለም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጉባኤ ፡ አይግባ ። ፭ ነገር ፡ ግን ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በለዓ ምን ፡ ይሰማ ፡ ዘንድ ፡ አልወደደም ፤ አምላክ ህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ወድዶሃልና ፡ እርግማ ፮ ኑን ፡ በረከት ፡ አደረገልህ ። በዘመንህ ፡ ሁሉ ፡ ለዘላለም ፡ ሰላምና ፡ ልማት ፡ ለእነርሱ ፡ አትሻ ።

፯ ኤዶማዊው ፡ ወንድምህ ፡ ነውና ፡ አትጸየ ፈው ፤ ግብፃዊውንም ፡ በአገሩ ፡ ስደተኛ ፡ ነበር ፰ ህና ፡ አትጸየፈው ። ከእነርሱም ፡ በሦስተኛው ፡ ትውልድ ፡ የሚወለዱ ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ እግዚአ ብሔር ፡ ጉባኤ ፡ ይግቡ ።

፱ ጠላቶችህን ፡ ልትወጋ ፡ በወጣህ ፡ ጊዜ ፡ ከክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ሰውነትህን ፡ ጠብቅ ። ፲ በእናንተ ፡ መካከል ፡ ሌሊት ፡ በሚሆነው ፡ ርኵ ሰት ፡ የረከሰ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ÷ ከሰፈር ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ይውጣ ÷ ወደ ፡ ሰፈርም ፡ አይግባ ። ፲፩ በመሸም ፡ ጊዜ ፡ በውኃ ፡ ይታጠብ ፤ ፀሐይም ፡ ፲፪ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሰፈር ፡ ይመለስ ። ወደ ፡ ሜዳም ፡ ትወጣበት ፡ ዘንድ ፡ ከሰፈር ፡ ውጭ ፡ ፲፫ ቦታ ፡ ይሁንልህ ። ከመሣሪያህም ፡ ጋር ፡ መቈ ፈሪያ ፡ ያዝ ፤ በሜዳም ፡ በተቀመጥህ ፡ ጊዜ ፡ ትምስበታለህ ÷ ዘረህም ፡ ከአንተ ፡ የወጣውን ፡ ፲፬ በአፈር ፡ ትከድነዋለህ ። አምላክህ ፡ እግዚአብ ሔር ፡ ሊያድንህ ፡ ጠላቶችህንም ፡ በእጅህ ፡ አሳልፎ ፡ ሊሰጥ ፡ በሰፈርህ ፡ መካከል ፡ ይሄዳ ልና ፡ ስለዚህ ፡ ነውረኛ ፡ ነገር ፡ እንዳያይብህ ÷ ፊቱንም ፡ ከአንተ ፡ እንዳይመልስ ፡ ሰፈርህ ፡ የተቀደሰ ፡ ይሁን ።

፲፭ ከጌታው ፡ ኰብልሎ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ የመጣ ውን ፡ ባሪያ ፡ ለጌታው ፡ አሳልፈህ ፡ አትስጥ ። ፲፮ ከደጆችህ ፡ በሚመርጣት ፡ በአንዲቱ ፡ በሚወ ድዳት ፡ ስፍራ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ በመካከልህ ፡ ይቀመጥ ÷ አንተም ፡ አታስጨንቀው ።

፲፯ ከእስራኤል ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ሴት ፡ ጋለ ሞታ ፡ አትገኝ ÷ ከእስራኤልም ፡ ወንዶች ፡ ፲፰ ልጆች ፡ ወንድ ፡ ጋለሞታ ፡ አይገኝ ። ስለ ፡ ተሳልኸው ፡ ስእለት ፡ ሁሉ ፡ የጋለሞታይቱን ፡ ዋጋና ፡ የውሻውን ፡ ዋጋ ፡ ወደ ፡ አምላክህ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አታቅርብ ፤ ሁለ ቱም ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የሚያጸይፉ ፡ ናቸውና ።

፲፱ ለወንድምህ ፡ በወለድ ፡ አታበድር ፤ የብር ፡ ወይም ፡ የእህል ፡ ወይም ፡ የማናቸውንም ፡ ነገር ፡ ፳ ሁሉ ፡ ወለድ ፡ አትውሰድ ። ለእንግዳው ፡ በወ ለድ ፡ አበድረው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አምላክህ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ ልትወርሳት ፡ በምትገባበት ፡ ምድር ፡ በሥራህ ፡ ሁሉ ፡ ይባርክህ ፡ ዘንድ ፡ ለወንድምህ ፡ በወለድ ፡ አታበድር ።

፳፩ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስእለት ፡ በተ ሳልህ ፡ ጊዜ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአ ንተ ፡ ፈጽሞ ፡ ይሻዋልና ÷ ኃጢአትም ፡ ይሆ ፳፪ ንብሃልና ፡ መክፈሉን ፡ አታዘገይ ። ብትሳል ፡ ፳፫ ግን ፡ ኃጢአት ፡ የለብህም ። በአፍህ ፡ የተናገር ኸውን ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በፈቃ ድህ ፡ ተስለሃልና ፡ ከከንፈርህ ፡ የወጣውን ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ ጠብቅ ።

፳፬ ወደ ፡ ባልንጀራህ ፡ ወይን ፡ ቦታ ፡ በገባህ ፡ ጊዜ ፡ እስክትጠግብ ፡ ድረስ ፡ ከወይኑ ፡ ብላ ፤ ወደ ፡ ዕቃህ ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ ምንም ፡ አታግባ ። ፳፭ ወደ ፡ ባልንጀራህ ፡ እርሻ ፡ በገባህ ፡ ጊዜ ፡ እሸ ቱን ፡ በእጅህ ፡ ቀጥፈህ ፡ ብላ ፤ ወዳልታጨ ደው ፡ ወደ ፡ ባልንጀራህ ፡ እህል ፡ ግን ፡ ማጭድ ፡ አታግባ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ ሰው ፡ ሴትን ፡ ወስዶ ፡ ቢያገባ ÷ የእፍረት ፡ ነገር ፡ ስላገኘባት ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ሞገስ ፡ ባታ ገኝ ÷ የፍችዋን ፡ ጽሕፈት ፡ ጽፎ ፡ በእጅዋ ፡ ፪ ይስጣት ÷ ከቤቱም ፡ ይስደዳት ። ከቤቱም ፡ ፫ ከወጣች ፡ በኋላ ፡ ሌላ ፡ ወንድ ፡ ብታገባ ÷ ሁለ ተኛውም ፡ ባል ፡ ቢጠላት ÷ የፍችዋንም ፡ ጽሕ ፈት ፡ ጽፎ ፡ በእጅዋ ፡ ቢሰጣት ÷ ከቤቱም ፡ ቢሰድዳት ÷ ወይም ፡ ሚስት ፡ አድርጎ ፡ ያገባት ፡ ፬ ሁለተኛው ፡ ባልዋ ፡ ቢሞት ÷ የሰደዳት ፡ የቀ ድሞ ፡ ባልዋ ፡ ከረከሰች ፡ በኋላ ፡ ደግሞ ፡ ያገ ባት ፡ ዘንድ ፡ አይገባውም ፤ ያ ፡ በእግዚአብሔር ፡ የተጠላ ፡ ነው ፤ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ የሰጠህን ፡ ምድር ፡ አታርክስ ።

፭ አዲስ ፡ ሚስትም ፡ ያገባ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ጦር ነት ፡ አይሂድ ÷ ነገርም ፡ አይጫኑበት ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ በቤቱ ፡ በፈቃዱ ፡ ይቀ መጥ ÷ የወሰዳትንም ፡ ሚስቱን ፡ ደስ ፡ ያሰኛት ።

፮ የሰውን ፡ ነፍስ ፡ እንደ ፡ መውሰድ ፡ ነውና ፡ ወፍጮ ፡ ወይም ፡ መጅ ፡ ስለ ፡ መያዣ ፡ ማንም ፡ አይውሰድ ።

፯ ማንም ፡ ሰው ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከወንድሞቹ ፡ አንዱን ፡ ሰርቆ ፡ እንደ ፡ ባሪያ ፡ ሲያደርግበት ፡ ወይም ፡ ሲሸጠው ፡ ቢገኝ ÷ ያ ፡ ሌባ ፡ ይሙት ፤ እንዲሁም ፡ ክፉውን ፡ ነገር ፡ ከመካከልህ ፡ ታስወግዳለህ ።

፰ በለምጽ ፡ ደዌ ፡ ሌዋውያን ፡ ካህናት ፡ ያስተማሩህን ፡ ሁሉ ፡ ፈጽመህ ፡ እንድትጠብቅ ፡ እንድታደርግም ፡ ተጠንቀቅ ፤ እኔ ፡ ያዘዝኋቸውን ፡ ፱ እንዲሁ ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ ጠብቅ ። አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከግብፅ ፡ በወጣችሁ ፡ ጊዜ ፡ በመንገድ ፡ ሳላችሁ ፡ በማርያም ፡ ላይ ፡ ያደረገውን ፡ አስብ ።

፲ ለባልንጀራህ ፡ ባበደርኸው ፡ ጊዜ ፡ መያዣ ፲፩ ውን ፡ ልትወስድ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ አትግባ ። አንተ ፡ በውጭ ፡ ቁም ፡ ያበደርኸውም ፡ ሰው ፡ መያዣ ፲፪ ውን ፡ ያውጣልህ ። ያም ፡ ሰው ፡ ድሀ ፡ ቢሆን ፡ ፲፫ መያዣውን ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ አታሳድር ። ለብሶት ፡ እንዲተኛ ፡ እንዲባርክህም ፡ ፀሐይ ፡ ሳይገባ ፡ መያዣውን ፡ ፈጽመህ ፡ መልስለት ፤ በአምላክህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ጽድቅ ፡ ይሆንልሃል

፲፬ ድሀና ፡ ችግረኛ ፡ የሆነውን ፡ ምንደኛ ÷ ከወንድሞችህ ፡ ወይም ፡ በምድርህ ፡ በአገርህ ፡ ደጅ ፡ ውስጥ ፡ ከሚቀመጡት ፡ መጻተኞች ፡ ቢሆን ÷ ፲፭ አታስጨንቀው ። ድሀ ፡ ነውና ÷ ነፍሱም ፡ ጠንክራ ፡ ትፈልገዋለችና ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳይጮኽብህ ፡ ኃጢአትም ፡ እንዳይሆንብህ ፡ ደመወዙን ፡ ፀሐይ ፡ ሳይገባ ፡ በቀኑ ፡ ስጠው ።

፲፮ አባቶች ፡ ስለ ፡ ልጆች ፡ አይገደሉ ÷ ልጆችም ፡ ስለ ፡ አባቶች ፡ አይገደሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ በኃጢአቱ ፡ ይገደል ።

፲፯ የመጻተኛውንና ፡ የድሀ ፡ አደጉን ፡ ፍርድ ፡ አታጣምምባቸው ፤ የመበለቲቱን ፡ ልብስ ፡ ለመ ፲፰ ያዣ ፡ አትውሰድባት ። አንተም ፡ በግብፅ ፡ ባሪያ ፡ እንደ ፡ ነበርህ ÷ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከዚያ ፡ እንዳዳነህ ፡ አስብ ፤ ስለዚህ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ አዝዝሃለሁ ።

፲፱ የእርሻህን ፡ መከር ፡ በጨድህ ፡ ጊዜ ፡ ነዶም ፡ ረስተህ ፡ በእርሻህ ፡ ብታስቀር ÷ ትወስደው ፡ ዘንድ ፡ አትመለስ ፤ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእጅህ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እንዲባርክህ ÷ ለመጻተ ፳ ኛና ፡ ለድሀ ፡ አደግ ፡ ለመበለትም ፡ ተወው ። የወይራህን ፡ ፍሬ ፡ ባረገፍህ ፡ ጊዜ ከቅርንጫፎቹ ፡ ላይ ፡ ማርገፉን ፡ ለማጣራት ፡ አትመለስ ፤ ለመጻተኛና ፡ ለድሀ ፡ አደግ ፡ ለመበለትም ፡ ይሁን ። ፳፩ የወይንህን ፡ ፍሬ ፡ በቈረጥህ ፡ ጊዜ ፡ ቃርሚያውን ፡ አትልቀመው ፤ ለመጻተኛና ፡ ለድሀ ፡ ፳፪ አደግ ፡ ለመበለትም ፡ ይሁን ። አንተም ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ ባሪያ ፡ እንደ ፡ ነበርህ ፡ አስብ ፤ ስለዚህ ፡ ይህን ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ አዝዝሃለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

፩ በሰዎች ፡ መካከል ፡ ጠብ ፡ ቢሆን ÷ ወደ ፡ ፍርድም ፡ ቢመጡ ÷ ፈራጆችም ፡ ቢፈርዱባቸው ÷ ጻድቁን ፡— ደኅና ፡ ነህ ÷ የበደለውንም ፡— በደ ፪ ለኛ ፡ ነህ ፡ ይበሉአቸው ። በደለኛውም ፡ መገረፍ ፡ ቢገባው ፡ እንዲገረፍ ፡ ፈራጁ ፡ በፊቱ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ያጋድመው ፤ የግርፋቱም ፡ ቍጥር ፡ እንደ ፡ ኃጢአቱ ፡ መጠን ፡ ይሁን ። ፫ ግርፋቱም ፡ አርባ ፡ ይሁን ፤ ከዚህ ፡ በላይ ፡ ጨምሮ ፡ ብዙ ፡ ግርፋት ፡ ቢገርፈው ፡ ወንድምህ ፡ በፊትህ ፡ ነውረኛ ፡ ይሆናልና ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ አይጨመርበት ።

፬ እህል ፡ የሚያበራየውን ፡ በሬ ፡ አፉን ፡ አትሰር ።

፭ ወንድማማቾች ፡ በአንድነት ፡ ቢቀመጡ ÷ አንዱም ፡ ልጅ ፡ ሳይኖረው ፡ ቢሞት ÷ የሞተው ፡ ሰው ፡ ሚስት ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ ታገባ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አትሂድ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የባልዋ ፡ ወንድም ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ገብቶ ፡ እርስዋን ፡ ያግባ ÷ ፮ ከእርስዋም ፡ ጋር ፡ ይኑር ። የምዋቹ ፡ ስም ፡ ከእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ እንዳይጠፋ ፡ ከእርስዋ ፡ የሚወለደው ፡ በኵር ፡ ልጅ ፡ በሞተው ፡ በወን ፯ ድሙ ፡ ስም ፡ ይጠራ ። ያም ፡ ሰው ፡ የወንድሙን ፡ ሚስት ፡ ማግባት ፡ ባይወድድ ÷ ዋርሳይቱ ፡ በበሩ ፡ አደባባይ ፡ ወደሚቀመጡ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሄዳ ፡— ዋርሳዬ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ለወንድሙ ፡ ስም ፡ ማቆም ፡ እንቢ ፡ አለ ፤ ከእኔ ፡ ፰ ጋር ፡ ሊኖርም ፡ አልወደደም ፡ ትበላቸው ። የከተማውም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ጠርተው ፡ ይጠይቁት ፤ እርሱም ፡ በዚያ ፡ ቆሞ ፡— አገባት ፡ ፱ ዘንድ ፡ አልወድድም ፡ ቢል ÷ ዋርሳይቱ ፡ በሽማግሌዎቹ ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀርባ ፡— የወንድሙን ፡ ቤት ፡ በማይሠራ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ እንዲህ ፡ ይደረግበታል ፡ ስትል ፡ ጫማውን ፡ ከእግሩ ፡ ታውጣ ÷ በፊቱም ፡ እንትፍ ፡ ትበልበት ። ፲ በእስራኤልም ፡ ዘንድ ፡ ስሙ ፡ የጫማ ፡ ፈቱ ፡ ቤት ፡ ተብሎ ፡ ይጠራ ።

፲፩ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ቢጣሉ ÷ የአንደኛውም ፡ ሚስት ፡ ባልዋን ፡ ከሚመታው ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ ታድነው ፡ ዘንድ ፡ ብትቀርብ ÷ እጅ ፲፪ ዋንም ፡ ዘርግታ ፡ ብልቱን ፡ ብትይዝ ÷ እጅዋን ፡ ቍረጥ ፤ ዓይንህም ፡ አትራራላት ።

፲፫ በከረጢትህ ፡ ውስጥ ፡ ታላቅና ፡ ታናሽ ፡ የሆነ ፡ ሁለት ፡ ዓይነት ፡ ሚዛን ፡ አይኑርልህ ። ፲፬ በቤትህ ፡ ውስጥ ፡ ታላቅና ፡ ታናሽ ፡ የሆነ ፡ ሁለት ፡ ዓይነት ፡ መስፈሪያ ፡ አይኑርልህ ። ፲፭፡፲፮ ይህን ፡ የሚያደርግ ፡ ሁሉ ፡ ክፋትንም ፡ የሚያደርግ ፡ ሁሉ ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተጠላ ፡ ነውና ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሚሰጥህ ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ ዕድሜህ ፡ ይረዝም ፡ ዘንድ ፡ እውነተኛና ፡ ፍጹም ፡ ሚዛን ፡ ይሁንልህ ፤ እውነተኛና ፡ ፍጹም ፡ መስፈሪያም ፡ ይሁንልህ ።

፲፯ ከግብፅ ፡ በወጣችሁ ፡ ጊዜ ፡ አማሌቅ ፡ በመን ፲፰ ገድ ፡ ላይ ፡ ያደረገብህን ፡ አስብ ፤ በመንገድ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተቃወመህ ÷ አንተም ፡ ተስኖህ ፡ ደክመህም ፡ ሳለህ ፡ ከአንተ ፡ በኋላ ፡ ደክመው ፡ የነበሩትን ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ መታ ፤ እግዚአብ

፲፱ ሔርንም ፡ አልፈራም ፡፡ ስለዚህ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትወርሳት ፡ ዘንድ ፡ በሚሰጥህ ፡ ምድር ፡ ከሚከብቡህ ፡ ጠላቶችህ ፡ ሁሉ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ባሳረፈህ ፡ ጊዜ ፥ የአማሌቅን ፡ ዝክረ ፡ ስሙን ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡ አጥፋው ፤ ይህንን ፡ አትርሳ ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ፡፡

፩ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ ወደሚሰጥህ ፡ ምድር ፡ በገባህም ፡ ጊዜ ፥ በወረ ፪ ስሃትም ፡ በኖርህባትም ፡ ጊዜ ፥ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሚሰጥህ ፡ ምድር ፡ ከምትሰበስበው ፡ ፍሬ ፡ ሁሉ ፡ በኵራት ፡ ውሰድ ፡ በዕንቅብም ፡ አድርገው ፥ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስሙ ፡ ይጠራበት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መረጠውም ፡ ስፍራ ፡ ፫ ይዘህ ፡ ሂድ ፡፡ በዚያም ፡ ወራት ፡ ወደሚሆነው ፡ ካህን ፡ መጥተህ ፡— እግዚአብሔር ፡ ይሰጠን ፡ ዘንድ ፡ ለአባቶቻችን ፡ ወደ ፡ ማለላቸው ፡ ምድር ፡ እንደ ፡ ገባሁ ፡ ዛሬ ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብ ፬ ሔር ፡ ፊት ፡ አስታውቃለሁ ፡ በለው ፡፡ ካህኑም ፡ ዕንቅቡን ፡ ከእጅህ ፡ ወስዶ ፡ በአምላክህ ፡ በእ ፭ ግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ፊት ፡ ያኑረው ፡፡ በአምላክህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ተናገር ፡— አባቴ ፡ የተቅበዘበዘ ፡ ሶርያዊ ፡ ነበረ ፤ በቍጥር ፡ ጥቂት ፡ ሳለ ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ወረደ ፡ በዚያም ፡ ተቀመጠ ፤ ታላቅ ፡ የሆነ ፡ የበረታም ፡ ቍጥሩም ፡ የበዛ ፡ ሕዝብ ፡ ሆነ ፡፡ ፮ ግብፃውያንም ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረጉብን ፥ አስ ጨነቁንም ፥ በላያችንም ፡ ጽኑ ፡ ከባድ ፡ ሥራን ፡ ፯ ጫኑብን ፡ ወደ ፡ አባቶቻችንም ፡ አምላክ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኽን ፤ እግዚአብሔርም ፡ ድምፃችንን ፡ ሰማ ፥ ጭንቀታችንንም ፡ ድካማች ፰ ንንም ፡ ግፋችንንም ፡ አየ ፤ እግዚአብሔርም ፡ በጸናች ፡ እጅና ፡ በተዘረጋ ፡ ክንድ ፥ በታላቅም ፡ ድንጋጤ ፥ በተአምራትም ፥ በድንቅም ፡ ከግ ፱ ብፅ ፡ አወጣን ፤ ወደዚህም ፡ ስፍራ ፡ አገባን ፥ ወተትና ፡ ማር ፡ የምታፈስሰውንም ፡ ይህችን ፡ ፲ ምድር ፡ ሰጠን ፡፡ አሁንም ፡ እነሆ ፥ አቤቱ ፥ አንተ ፡ የሰጠኸኝን ፡ የምድሪቱን ፡ ፍሬ ፡ በኵራት ፡ አቅርቤአለሁ ፡፡ አንተም ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አኑረው ፥ በአምላክ ፲፩ ህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ስገድ ፡፡ አንተም ፡ በመካከልህም ፡ ያለ ፡ ሌዋዊና ፡ መጻተኛ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአንተና ፡ ለቤትህ ፡ በሰጠው ፡ ቸርነት ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡፡

፲፪ እሥራት ፡ በምታወጣበት ፡ በሦስተኛው ፡ ዓመት ፡ የፍሬህን ፡ ሁሉ ፡ እሥራት ፡ አውጥተህ ፡ በፈጸምህ ፡ ጊዜ ፥ በአገርህ ፡ ደጅ ፡ ውስጥ ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ ይጠግቡም ፡ ዘንድ ፡ ለሌዋዊው ፡ ለመጻተኛውም ፡ ለድሀ ፡ አደጉም ፡ ለመበለቲ ፲፫ ቱም ፡ ስጣቸው ፡፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንዲህ ፡ በል ፡— የተቀደሰውን ፡ ነገር ፡ ከቤቴ ፡ ወስጄ ፡ ለሌዋዊው ፡ ለመጻተኛውም ፡ ለድሀ ፡ አደጉም ፡ ለመበለቲቱም ፡ እንዳዘዝኸኝ ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ሰጥቼአለሁ ፤ ትእዛዝህን ፡ ምንም ፡ አላፈረስሁም ፥ አልረሳሁምም ፤ ፲፬ በኀዘኔ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ ከእርሱ ፡ አልበላሁም ፥ ስርኵስነቴም ፡ ከእርሱ ፡ አላወጣሁም ፥ ከእርሱም ፡ አንዳች ፡ ለሞተ ፡ ሰው ፡ አልሰጠሁም ፤ የአምላኬንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ሰምቼአለሁ ፥ ያዘዝኸኝንም ፡ ሁሉ ፡ አድርጌአለሁ ፡፡ ፲፭ ከቅዱስ ፡ ማደሪያህ ፡ ከሰማይ ፡ ጐብኝ ፥ ሕዝብህንም ፡ እስራኤልን ፡ ለአባቶቻችን ፡ እንደ ፡ ማልህላቸው ፡ የሰጠኸንንም ፡ ወተትና ፡ ማር ፡ የምታፈስሰውን ፡ አገር ፡ ባርክ ፡፡

፲፮ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ ዛሬ ፡ አዝዞሃል ፤ አንተም ፡ በፍጹም ፡ ልብህና ፡ በፍጹም ፡ ነፍስህ ፡ ጠብቀው ፥ አድርገውም ፡፡ ፲፯ አንተ ፡ በመንገዱ ፡ ትሄድ ፡ ዘንድ ፥ ሥርዓቱንና ፡ ትእዛዙን ፡ ፍርዱንም ፡ ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፥ ቃሉንም ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ እርሱ ፡ አምላክህ ፡ መሆኑን ፡ ዛሬ ፡ አስታውቀሃል ፡፡ ፲፰ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ሰጠህ ፡ ተስፋ ፡ ገንዘቡና ፡ ሕዝቡ ፡ መሆንህን ፥ ትእዛዙንም ፡ ሁሉ ፡ ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፥ ፲፱ ከፈጠራቸውም ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ በምስጋና ፡ በስም ፡ በክብር ፡ ከፍ ፡ ያደርግህ ፡ ዘንድ ፥ እርሱም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ ፡ ሕዝብ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ዛሬ ፡ አስታውቆአል ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ፡፡

፩ ሙሴና ፡ የእስራኤል ፡ ሽማግሌዎችም ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ ሕዝቡን ፡ አዘዙ ፡— ዛሬ ፡ ያዘዝኋችሁን ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ጠብቁ ፡፡ ፪ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደሚሰጥህ ፡ ምድር ፡ ዮርዳኖስን ፡ በተሻገርህ ፡ ጊዜ ፡ ታላላቅ ፡ ድንጋዮችን ፡ ለአንተ ፡ አቁም ፥ በኖራም ፡ ምረጋቸው ፡፡ ፫ የአባቶችህ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተስፋ ፡ እንደ ፡ ሰጠህ ፥ ወተትና ፡ ማር ፡ ወደምታፈስስ ፡ ምድር ፥ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደሚሰጥህ ፡ ምድር ፡ ትገባ ፡ ዘንድ ፡ በተሻገርህ ፡ ጊዜ ፥ የዚህን ፡ ሕግ ፡ ቃሎች ፡ ሁሉ ፡ ጻፍባቸው ፡፡ ፬ ዮርዳኖስንም ፡ በተሻገርህ ፡ ጊዜ ፥ ዛሬ ፡ እንዳዘዝሁህ ፥ እነዚህን ፡ ድንጋዮች ፡ በጌባል ፡ ተራራ ፡ አቁም ፥ በኖራም ፡ ምረጋቸው ፡፡ ፭ በዚያም ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ሥራ ፤ መሠዊያውም ፡ ብረት ፡ ካልነካው ፡ ድንጋይ ፡ ይሁን ፡፡ ፮ ካልተጠረበም ፡ ድንጋይ ፡ የአምላክህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መሠዊያ ፡ ሥራ ፤ ለአምላክም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትህን ፡ አቅርብበት ፡ ፯ የደኅንነትም ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዋበት ፥ በዚያም ፡ ብላ ፤ በአምላክህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ደስ ፡ ይበልህ ፡፡ ፰ የዚህንም ፡ ሕግ ፡ ቃሎች ፡ ሁሉ ፡ የተገለጠ ፡ አድርገህ ፡ በድንጋዮቹ ፡ ላይ ፡ ጻፍ ፡፡

፱ ሙሴና ፡ ሌዋውያን ፡ ካህናት ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ ተናገሩ ፡— እስራኤል ፡

ሆይ ÷ ዝም ፡ ብላችሁ ፡ አድምጡ ፤ ዛሬ ፡ የአ
ምላክህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡ ሆነሃል ።
፲ ለአምላክህም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ታዘዝ ÷
ዛሬም ፡ የማዝዝህን ፡ ትእዛዙንና ፡ ሥርዓቱን ፡
አድርግ ።

፲፩ ሙሴም ፡ በዚያን ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ሕዝ
፲፪ ቡን ፡ አዘዘ ፡— ዮርዳኖስን ፡ በተሻገራችሁ ፡
ጊዜ ፡ ሕዝቡን ፡ ይባርኩ ፡ ዘንድ ፡ እነዚህ ÷ ስም
ዖንና ፡ ሌዊ ፡ ይሁዳና ፡ ይሳኮር ፡ ዮሴፍና ፡ ብን
፲፫ ያም ÷ በገሪዛን ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ይቁሙ ። ይረግ
ሙም ፡ ዘንድ ፡ እነዚህ ÷ ሮቤልና ፡ ጋድ ፡ አሴ
ርና ፡ ዛብሎን ፡ ዳንና ፡ ንፍታሌም ÷ በጌባል ፡
፲፬ ተራራ ፡ ላይ ፡ ይቁሙ ። ሌዋውያንም ፡ ከፍ ፡
ባለች ፡ ድምፅ ፡ ለእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
እንዲህ ፡ ብለው ፡ ይናገራሉ ፡—

፲፭ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተጠላ ፡ የሠራተኛ ፡
እጅ ፡ ሥራን ፡ የተቀረጸ ፡ ወይም ፡ ቀልጦ ፡ የተ
ሠራ ፡ ምስልን ፡ የሚያደርግ ÷ በስውርም ፡ የሚ
ያቆመው ፡ ሰው ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፤ ሕዝቡም ፡
ሁሉ ፡ መልሰው ፡ አሜን ፡ ይላሉ ።

፲፮ አባቱን ፡ ወይም ፡ እናቱን ፡ የሚያቃልል ፡
ርጉም ፡ ይሁን ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡
ይላሉ ።

፲፯ የባልንጀራውን ፡ የድንበር ፡ ምልክት ፡ የሚ
ገፋ ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡
ይላሉ ።

፲፰ ዕውሩን ፡ ከመንገድ ፡ ፈቀቅ ፡ የሚያደርግ ፡
ርጉም ፡ ይሁን ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡
ይላሉ ።

፲፱ በመጻተኛ ፡ በድሀ ፡ አደጉም ፡ በመበለቲ
ቱም ፡ ላይ ፡ ፍርድን ፡ የሚያጣምም ፡ ርጉም ፡
ይሁን ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡ ይላሉ ።

፳ ከአባቱ ፡ ሚስት ፡ ጋር ፡ የሚተኛ ፡ የአባቱን ፡
ልብስ ፡ ገልጦአልና ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፤ ሕዝቡም ፡
ሁሉ ፡ አሜን ፡ ይላሉ ።

፳፩ ከማናቸይቱም ፡ እንስሳ ፡ ጋር ፡ የሚተኛ ፡
ርጉም ፡ ይሁን ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡ ይላሉ ።

፳፪ ከአባቱ ፡ ወይም ፡ ከእናቱ ፡ ልጅ ፡ ከእኅቱ ፡
ጋር ፡ የሚተኛ ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፤ ሕዝቡም ፡
ሁሉ ፡ አሜን ፡ ይላሉ ።

፳፫ ከአማቱ ፡ ጋር ፡ የሚተኛ ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፤
ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡ ይላሉ ።

፳፬ ባልንጀራውን ፡ በስውር ፡ የሚመታ ፡ ርጉም ፡
ይሁን ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡ ይላሉ ።

፳፭ የንጹሑን ፡ ሰው ፡ ነፍስ ፡ ለመግደል ፡ ጉቦ ፡
የሚቀበል ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡
አሜን ፡ ይላሉ ።

፳፮ የዚህን ፡ ሕግ ፡ ቃሎች ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ የማ
ያጸና ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡
ይላሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

፩ እንዲህም ፡ ይሆናል ፤ የአምላክህን ፡ የእግዚ
አብሔርን ፡ ቃል ፡ ብትሰማ ÷ ዛሬም ፡ ያዘዝሁ
ህን ፡ ትእዛዙን ፡ ሁሉ ፡ ብታደርግ ፡ ብትጠብ
ቅም ÷ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከምድር ፡
አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርግሃል ።
፪ የአምላክህንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ብት
ሰማ ፡ እነዚህ ፡ በረከቶች ፡ ሁሉ ፡ ይመጡልሃል ፡
፫ ያገኙህማል ። አንተ ፡ በከተማ ፡ ቡሩክ ፡ ትሆና
፬ ለህ ÷ በእርሻም ፡ ቡሩክ ፡ ትሆናለህ ። የሆድህ ፡
ፍሬ ÷ የምድርህም ፡ ፍሬ ÷ የከብትህም ፡ ፍሬ ÷
የላምህም ፡ ርቢ ÷ የበግህም ፡ ርቢ ፡ ቡሩክ ፡
፭ ይሆናል ። እንቅብህና ፡ ቡሃቃህ ፡ ቡሩክ ፡ ይሆ
፮ ናል ። አንተም ፡ በመግባትህ ፡ ቡሩክ ፡ ትሆና
ለህ ÷ በመውጣትህም ፡ ቡሩክ ፡ ትሆናለህ ።

፯ እግዚአብሔርም ፡ በላይህ ፡ የሚቆሙትን ፡
ጠላቶችህን ፡ በፊትህ ፡ የተመቱ ፡ ያደርጋቸ
ዋል ፤ በአንድ ፡ መንገድ ፡ ይመጡብሃል ÷ በሰባ
፰ ትም ፡ መንገድ ፡ ከፊትህ ፡ ይሸሻሉ ። እግዚአ
ብሔር ፡ በረከቱ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ በጐተራህ ፡
በእጅህም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እንዲወርድ ፡ ያዝ
ዛል ፤ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሚሰጥህም ፡
፱ ምድር ፡ ይባርክሃል ። የአምላክህን ፡ የእግዚ
አብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ብትጠብቅ ÷ በመንገ
ዱም ፡ ብትሄድ ÷ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ማለ
ልህ ፡ ለእርሱ ፡ የተቀደሰ ፡ ሕዝብ ፡ አድርጎ ፡
፲ ያቆምሃል ። የምድር ፡ አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ የእግ
ዚአብሔር ፡ ስም ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተጠራ ፡
፲፩ አይተው ፡ ይፈሩሃል ። እግዚአብሔርም ፡ እር
ስዋን ፡ ይሰጥህ ፡ ዘንድ ፡ ለአባቶችህ ፡ በማለላ
ቸው ፡ በምድርህ ፡ ላይ ÷ በሆድህ ፡ ፍሬ ÷ በከብ
ትህ ፡ ፍሬ ÷ በእርሻህም ፡ ፍሬ ÷ እግዚአብሔር ፡
፲፪ በጎነትን ፡ በላይህ ፡ ያበዛል ። እግዚአብሔርም ፡
ለምድርህ ፡ በወራቱ ፡ ዝናብ ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ÷
የእጅህንም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ይባርክ ፡ ዘንድ ፡
መልካሙን ፡ መዝገብ ፡ ሰማዩን ፡ ይከፍትልሃል ፤
ለብዙ ፡ አሕዛብም ፡ ታበድራለህ ÷ አንተ ፡ ግን ፡
፲፫፡፲፬ ከማንም ፡ አትበደርም ። ዛሬም ፡ ያዘዝሁህን ፡
የአምላክህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ሰም
ተህ ፡ ብትጠብቃት ፡ ብታደርጋትም ÷ ዛሬም ፡
ካዘዝሁህ ፡ ከእነዚህ ፡ ቃሎች ፡ ወደ ፡ ቀኝ ፡ ወደ ፡
ግራም ፡ ፈቀቅ ፡ በትል ÷ ታመልካቸውም ፡
ዘንድ ፡ ሌሎችን ፡ አማልክት ፡ በትከተል ÷ እግ
ዚአብሔር ፡ ራስ ፡ ያደርግሃል ፡ እንጂ ፡ ጅራት ፡
አያደርግህም ፤ ሁልጊዜም ፡ በላይ ፡ እንጂ ፡
በታች ፡ አትሆንም ።

፲፭ ነገር ፡ ግን ፡ የአምላክህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ቃል ፡ ባትሰማ ÷ ዛሬም ፡ ያዘዝሁህን ፡ ሥርዓ
ቱንና ፡ ትእዛዙን ፡ ሁሉ ፡ በትጠብቅ ፡ በታደር
ግም ÷ እነዚህ ፡ መርገሞች ፡ ሁሉ ፡ ይመጡብ
፲፮ ሃል ፡ ያገኙህማል ። በከተማ ፡ ርጉም ፡ ትሆና
፲፯ ለህ ÷ በእርሻም ፡ ርጉም ፡ ትሆናለህ ። እንቅብ
፲፰ ህና ፡ ቡሃቃህ ፡ ርጉም ፡ ይሆናል ። የሆድህ ፡
ፍሬ ÷ የምድርህም ፡ ፍሬ ÷ የላምህም ፡ ርቢ ÷
፲፱ የበግህም ፡ ርቢ ፡ ርጉም ፡ ይሆናል ። አንተ ፡
በመግባትህ ፡ ርጉም ፡ ትሆናለህ ÷ በመውጣት
፳ ህም ፡ ርጉም ፡ ትሆናለህ ። እኔን ፡ ስለ ፡ ተው

ሽኝ ፥ ስለ ፡ ሥራህ ፡ ክፋት ፥ እስክትጠፋ ፡
ፈጥነህም ፡ እስክታልቅ ፡ ድረስ ፡ በምትሠ
ራው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ መርገ
ምን ፥ ሽሽትን ፥ ተግሣጽን ፥ ይሰድድብሃል ።
፳፩ እግዚአብሔር ፡ ትወርሳት ፡ ዘንድ ፡ ከምትገባ
ባት ፡ ምድር ፡ እስኪያጠፋህ ፡ ድረስ ፡ ቸነፈ
፳፪ ርን ፡ ያጣብቅብሃል ። እግዚአብሔር ፡ በክሳት ፥
በንዳድም ፥ በጥብሳትም ፥ በትኵሳትም ፥ በድ
ርቅም ፥ በዋግም ፥ በአረማሞም ፡ ይመታሃል ፤
፳፫ እስክትጠፋም ፡ ድረስ ፡ ያሳድዱሃል ። በራስ
ህም ፡ ላይ ፡ ሰማይ ፡ ናስ ፡ ይሆንብሃል ፥ ከእግር
ህም ፡ በታች ፡ ምድሪቱ ፡ ብረት ፡ ትሆንብሃለች ።
፳፬ እግዚአብሔር ፡ የምድርህን ፡ ዝናብ ፡ ትቢያና ፡
አፈር ፡ ያደርጋል ፤ እስክትጠፋ ፡ ድረስ ፡ ከሰ
ማይ ፡ ይወርድብሃል ።

፳፭ እግዚአብሔር ፡ ከጠላቶችህ ፡ ፊት ፡ የተመ
ታህ ፡ ያደርግሃል ፤ በአንድ ፡ መንገድ ፡ ትወጣ
በቸዋለህ ፥ በሰባት ፡ መንገድ ፡ ከእነርሱ ፡ ትሸ
ሻለህ ፤ ለምድርም ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ ድን
፳፮ ጋጤ ፡ ትሆናለህ ። ሬሳህ ፡ ለሰማይ ፡ ወፎች ፡
ሁሉ ፡ ለምድርም ፡ አራዊት ፡ መብል ፡ ይሆናል ፥
፳፯ የሚያስፈራቸውም ፡ የለም ። እግዚአብሔር ፡
ፈውስ ፡ በሌለው ፡ በግብፅ ፡ ቍስል ፡ በእበጭም ፡
፳፰ በቋቁቻም ፡ በችፌም ፡ ይመታሃል ። እግዚአ
ብሔር ፡ በዕብደት ፥ በዕውርነት ፥ በድንጋጤም ፡
፳፱ ይመታሃል ። በቀትርም ፡ ጊዜ ፡ ዕውር ፡ በጨ
ለማ ፡ እንደሚርመሰመስ ፡ ትርመሰመሳለህ ፥
መንገድህም ፡ የቀና ፡ አይሆንም ፤ በዘመንህም ፡
ሁሉ ፡ የተጨነቅህ ፡ የተዘረፍህም ፡ ትሆናለህ ፥
፴ የሚያድንህም ፡ የለም ። ሚስት ፡ ታጫለህ ፥
ሌላም ፡ ሰው ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ ይተኛል ፤ ቤት ፡
ትሠራለህ ፥ አትቀመጥበትም ፤ ወይን ፡ ትተክ
፴፩ ላለህ ፥ ከእርሱም ፡ አትበላም ። በሬህ ፡ በፊ
ትህ ፡ ይታረዳል ፥ ከእርሱም ፡ አትበላም ፤ አህ
ያህ ፡ ከእጅህ ፡ በግድ ፡ ይወሰዳል ፥ ወደ ፡ አን
ተም ፡ አይመለስም ፤ በግህ ፡ ለጠላቶችህ ፡ ትሰ
፴፪ ጣለች ፥ የሚያድንህም ፡ አታገኝም ። ወንዶ
ችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆችህ ፡ ለሌላ ፡ ሕዝብ ፡
ይሰጣሉ ፥ ዓይኖችህም ፡ ያያሉ ፥ ሁልጊዜም ፡
ስለ ፡ እነርሱ ፡ ሲባክኑ ፡ ያልቃሉ ፤ በእጅህም ፡
፴፫ ኃይል ፡ ምንም ፡ አይገኝም ። የምድርህን ፡ ፍሬ ፡
ድካምህንም ፡ ሁሉ ፡ የማታውቀው ፡ ሕዝብ ፡
ይበላዋል ፤ አንተም ፡ ሁልጊዜ ፡ የተጨነቅህ ፡
፴፬ የተገፋህም ፡ ትሆናለህ ። ዓይኖችህም ፡ ከሚያ
፴፭ ዩት ፡ የተነሣ ፡ ዕብድ ፡ ትሆናለህ ። እግዚአብ
ሔር ፡ ፈውስ ፡ በሌለው ፡ በክፉ ፡ ቍስል ፡ ጕል
በትህንና ፡ ጭንህን ፡ ከእግርህ ፡ ጫማ ፡ እስከ ፡
አናትህ ፡ ድረስ ፡ ይመታሃል ።

፴፮ እግዚአብሔርም ፡ አንተን ፡ በአንተም ፡ ላይ ፡
የምታነግሠውን ፡ ንጉሥ ፡ አንተና ፡ አባቶችህ ፡
ወዳላወቃችኋቸው ፡ ሕዝብ ፡ ይወስድሃል ፤ በዚ
ያም ፡ ሌሎችን ፡ የእንጨትና ፡ የድንጋይ ፡ አማ
፴፯ ልክት ፡ ታመልካለህ ። እግዚአብሔርም ፡ በሚ
ያገባህ ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ሁሉ ፡ ድንጋጤ ፡
ምሳሌም ፡ ተረትም ፡ ትሆናለህ ። እጅግ ፡ ዘር ፡ ፴፰
ወደ ፡ እርሻ ፡ ታወጣለህ ፤ አንበጣም ፡ ይበላዋ
ልና ፡ ጥቂት ፡ ትሰበስባለህ ። ወይን ፡ ትተክላ ፴፱
ለህ ፡ ታበጀውማለህ ፡ ትልም ፡ ይበላዋልና ፡
ከእርሱ ፡ ምንም ፡ አትሰበስብም ፥ የወይን ፡
ጠጁንም ፡ አትጠጣም ። የወይራ ፡ ዛፍ ፡ በአገ ፵
ርህ ፡ ሁሉ ፡ ይሆንልሃል ፤ ወይራህም ፡ ይረግፋ
ልና ፡ ዘይቱን ፡ አትቀባም ። ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ፵፩
ልጆች ፡ ይወለዱልሃል ፤ በምርኮም ፡ ይሄዳሉና ፡
ለአንተ ፡ አይሆኑልህም ። ዛፍህን ፡ ሁሉ ፡ የም ፵፪
ድርህንም ፡ ፍሬ ፡ ኩብኩብ ፡ ይወርሰዋል ። በአ ፵፫
ንተ ፡ መካከል ፡ ያለ ፡ መጻተኛ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡
ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ፥ አንተም ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ ትላ
ለህ ። እርሱ ፡ ያበድርሃል ፥ አንተ ፡ ግን ፡ አታ ፵፬
በድረውም ፤ እርሱ ፡ ራስ ፡ ይሆናል ፥ አንተም ፡
ጅራት ፡ ትሆናለህ ። የአምላክህንም ፡ የእግዚ ፵፭
አብሔርን ፡ ቃል ፡ ስላልሰማህ ፥ ያዘዘህንም ፡
ትእዛዙንና ፡ ሥርዓቱን ፡ ስላልጠበቅህ ፥ እስክ
ትጠፋ ፡ ድረስ ፡ እነዚህ ፡ መርገሞች ፡ ሁሉ ፡
ይወርዱብሃል ፥ ያሳድዱህማል ፥ ያገኙህማል ።
በአንተም ፡ በልጅ ፡ ልጅህም ፡ ላይ ፡ ለዘላለም ፡ ፵፮
ለምልክትና ፡ ለድንቅ ፡ ይሆናሉ ።

ሁሉን ፡ አብዝቶ ፡ ስለ ፡ ሰጠህ ፡ አምላክህን ፡ ፵፯
እግዚአብሔርን ፡ በፍሥሐና ፡ በሐሤት ፡ አላመለ
ክህምና ፡ በራብና ፡ በጥማት ፡ በዕራቁትነትም ፡ ፵፰
ሁሉንም ፡ በማጣት ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሚልክ
ብህ ፡ ለጠላቶችህ ፡ ትገዛለህ ፤ እስኪያጠፋህም ፡
ድረስ ፡ በአንገትህ ፡ ላይ ፡ የብረት ፡ ቀንበር ፡
ይጭናል ። እግዚአብሔር ፡ ቋንቋቸውን ፡ የማ ፵፱፶
ታውቀውን ፥ ፊታቸው ፡ የደነደነውን ፥ ሽማ
ግሌውንም ፡ የማያፍሩትን ፥ ሕፃኑንም ፡ የማይ
ምሩትን ፡ ሕዝብ ፡ ንስር ፡ እንደሚበርር ፡ ከሩቅ ፡
አገር ፡ ከምድር ፡ ዳር ፡ ያመጣብሃል ። እስክት ፶፩
ጠፋ ፡ ድረስ ፡ የከብትህን ፡ ፍሬ ፡ የምድርህንም ፡
ፍሬ ፡ ይበላሉ ፤ እስኪያጠፉህም ፡ ድረስ ፡ እህ
ልን ፡ የወይንም ፡ ጠጅ ፡ ዘይትንም ፡ የላምህንና ፡
የበግህን ፡ ርቢ ፡ አይተዉልህም ። በአገርህ ፡ ፶፪
ሁሉ ፡ ያሉ ፥ ትታመንባቸው ፡ የነበሩ ፥ የረ
ዘሙ ፡ የጸኑም ፡ ቅጥሮች ፡ እስኪፈርሱ ፡ ድረስ ፥
በከተሞችህ ፡ ደጆች ፡ ሁሉ ፡ ከብበው ፡ ያስጨ
ንቁሃል ፤ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ በሰጠህ ፡
ምድር ፡ ሁሉ ፡ በደጆች ፡ ሁሉ ፡ ከብበው ፡ ያስ
ጨንቁሃል ። ጠላቶችህም ፡ ከብበው ፡ በስጨነ ፶፫
ቁህና ፡ መከራ ፡ በሳዩህ ፡ ጊዜ ፡ አምላክህ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ የሚሰጥህን ፡ የሆድህን ፡ ፍሬ ፡ የወ
ንዶችና ፡ የሴቶች ፡ ልጆችህን ፡ ሥጋ ፡ ትበላ
ለህ ። በአንተ ፡ ዘንድ ፡ የተለሳለሰና ፡ በቅምጥ ፶፬
ልነት ፡ ሁልጊዜ ፡ ይኖር ፡ የነበረ ፡ ሰው ፡ በወን
ድሙ ፥ አቅፋውም ፡ በምትተኛ ፡ በሚስቱ ፥
በቀሩትም ፡ ልጆች ፡ ይቀናል ፤ በደጆችህ ፡ ፶፭
ሁሉ ፡ ውስጥ ፡ ጠላቶችህ ፡ ከብበው ፡ በስጨነ
ቁህና ፡ መከራ ፡ በሳዩህ ፡ ጊዜ ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡ የቀ
ረው ፡ የለምና ፡ ከሚበላው ፡ ከልጆቹ ፡ ሥጋ ፡
ለአንዱ ፡ አይሰጥም ። በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ያለ ፶፮

ችው ፡ የተለሳለሰችና ፡ በቅምጥልነት ፡ ሁል ጊዜ ፡ ትኖር ፡ የነበረችው ፥ ከልስላሴና ፡ ከቅምጥልነት ፡ የተነሣ ፡ የእግር ፡ ጫማዋን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ያላደረገችው ፡ ሴት ፥ አቅፋ ፡ በተኛችው ፡ ባልዋ ፥ በወንድና ፡ በሴት ፡ ልጅዋም ፥ ፶፯ በእግርዋ ፡ መካከል ፡ በሚወጣው ፡ በእንግዴ ፡ ልጅ ፥ በምትወልዳቸውም ፡ ልጆች ፡ ትቀናለች ፤ በደጆችህም ፡ ውስጥ ፡ ጠላቶችህ ፡ ከብበው ፡ በስጨነቁህና ፡ መከራ ፡ በሰዩህ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉን ፡ ስላጣች ፡ በስውር ፡ ትበላቸዋለች ።

፶፰ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፉትን ፡ የዚህን ፡ ሕግ ፡ ቃሎች ፡ ሁሉ ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ በትጠብቅ ፥ ይህንንም ፡ «አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡» የተባለውን ፡ የተመሰገነውንና ፡ የተፈራውን ፡ ስም ፡ ፶፱ በትፈራ ፥ እግዚአብሔር ፡ መቅሠፍትህን ፥ የዘርህንም ፡ መቅሠፍት ፥ ብዙ ፡ ዘመንም ፡ የሚኖረውን ፡ ታላቅ ፡ መቅሠፍት ፥ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ፷ የሚኖረውንም ፡ ክፉ ፡ ደዌ ፡ ያደርግብሃል ። የፈራኸውንም ፡ የግብፅ ፡ ደዌ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ፷፩ ያመጣብሃል ፥ ይጣበቅብህማል ። ደግሞም ፡ ይህ ፡ ሕግ ፡ ባለበት ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ ያልተጻፈውን ፡ ደዌ ፡ ሁሉ ፡ መቅሠፍትም ፡ ሁሉ ፡ እስክትጠፋ ፡ ድረስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያመጣብ ፷፪ ሃል ። የአምላካችሁን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አልሰማችሁምና ፡ ከብዛታችሁ ፡ የተነሣ ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከዋክብት ፡ የነበረው ፡ ቍጥራችሁ ፡ ፷፫ ጥቂት ፡ ሆኖ ፡ ይቀራል ። እግዚአብሔርም ፡ በጎ ፡ ያደርግላችሁ ፡ ዘንድ ፡ ያበዛችሁም ፡ ዘንድ ፡ ደስ ፡ ይለው ፡ እንደ ፡ ነበረ ፥ እንዲሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሲያጠፋችሁ ፡ ሲያፈርሳችሁም ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤ ትወርሱአትም ፡ ዘንድ ፡ ከምትገቡ ፷፬ ባት ፡ ምድር ፡ ትነቀላላችሁ ። እግዚአብሔርም ፡ ከምድር ፡ ዳር ፡ እስከ ፡ ዳርቻዋ ፡ ድረስ ፡ ወዳሉ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ይበትንሃል ፤ በዚያም ፡ አንተና ፡ አባቶችህ ፡ ያላወቃችኋቸውን ፡ ሌሎችን ፡ አማልክት ፥ እንጨትንና ፡ ድንጋይን ፥ ፷፭ ታመልካለህ ። በእነዚያም ፡ አሕዛብ ፡ መካከል ፡ ዕረፍት ፡ አታገኝም ፥ ለእግርህም ፡ ጫማ ፡ ማረፊያ ፡ አይሆንም ፤ በዚያም ፡ እግዚአብሔር ፡ ተንቀጥቃጭ ፡ ልብ ፥ ፈዛዛ ፡ ዓይን ፥ ደካማም ፡ ፷፮ ነፍስ ፡ ያመጣብሃል ። ነፍስህም ፡ ታመነታለች ፤ ሌሊትና ፡ ቀንም ፡ ትፈራለህ ፥ በሕይወትህም ፡ ፷፯ አትታመንም ፤ አንተ ፡ ስለ ፡ ፈራህበት ፡ ስለ ፡ ልብህ ፡ ፍርሃት ፥ በዓይንህም ፡ ስለምታየው ፡ አስተያየት ፥ ማለዳ ፡— መቼ ፡ ይመሻል ? ትላ ፷፰ ለህ ፤ ማታም ፡— መቼ ፡ ይነጋል ? ትላለህ ። ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ተመልሰህ ፡ አታያትም ፡ ባልሁህ ፡ መንገድም ፡ እግዚአብሔር ፡ በመርከብ ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ይመልስሃል ፤ በዚያም ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ባሪያዎች ፡ ትሆኑአቸው ፡ ዘንድ ፡ ለጠላቶቻችሁ ፡ ራሳችሁን ፡ ትሸጣላችሁ ፤ የሚገዛችሁም ፡ አይገኝም ።

ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

፩ እግዚአብሔር ፡ በኮሬብ ፡ ካደረገው ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ሌላ ፡ በሞዓብ ፡ ምድር ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ ያደርገው ፡ ዘንድ ፡ ሙሴን ፡ ያዘዘው ፡ የቃል ፡ ኪዳኑ ፡ ቃሎች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።

፪ ሙሴም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ጠርቶ ፡ አላቸው ፡— እግዚአብሔር ፡ በፊታችሁ ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ በፈርዖንና ፡ በባሪያዎቹ ፡ ሁሉ ፡ ፫ በምድሩም ፡ ሁሉ ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፥ ዓይኖቻችሁ ፡ ያዩአቸውን ፡ ታላላቆች ፡ ፈተናዎች ፥ ታላላቆች ፡ ተአምራትና ፡ ድንቆች ፥ አይታችኋል ፤ ፬ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ አስተዋይ ፡ ልብ ፥ የሚያዩ ፡ ዓይኖች ፥ የሚሰሙም ፡ ጆሮች ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ አልሰጣችሁም ። ፭ አርበ ፡ ዓመት ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ መራኋችሁ ፤ ልብሳችሁም ፡ አላረጀባችሁም ፥ ጫማችሁም ፡ በእግራችሁ ፡ ላይ ፡ አላረጀም ። ፮ እኔ ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ እንጀራ ፡ አልበላችሁም ፥ የወይን ፡ ጠጅና ፡ የሚያሰክረውን ፡ መጠጥ ፡ አልጠጣችሁም ። ፯ ወደዚህም ፡ ስፍራ ፡ በመጣችሁ ፡ ጊዜ ፡ የሐሴቦን ፡ ንጉሥ ፡ ሴዎን ፡ የባሳንም ፡ ንጉሥ ፡ ዐግ ፡ ሊወጉን ፡ ወጡብን ፥ እኛም ፡ መታናቸው ፤ ፰ ምድራቸውንም ፡ ወስደን ፡ ለሮቤልና ፡ ለጋድ ፡ ለምናሴም ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ርስት ፡ አድርገን ፡ ሰጠናቸው ። ፱ ስለዚህ ፡ በምታደርጉት ፡ ሁሉ ፡ ትከናወኑ ፡ ዘንድ ፡ የዚህን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ቃሎች ፡ ጠብቁ ፡ አድርጉም ። ፲፥፲፩ ሁላችሁ ፥ አለቆቻችሁም ፡ ነገዶቻችሁም ፡ ሽማግሌዎቻችሁም ፡ ሹማምቶቻችሁም ፥ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ልጆቻችሁም ፡ ሴቶቻችሁም ፡ በሰፈራችሁም ፡ ያለ ፡ እንጨትህን ፡ የሚቈርጥ ፡ ውኃህንም ፡ የሚቀዳ ፡ መጻተኛ ፥ ዛሬ ፡ በአምላካችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቆማችኋል ፤ ፲፪፥፲፫ ይኸውም ፡ ዛሬ ፡ ለእርሱ ፡ ሕዝብ ፡ አድርጎ ፡ ያስነሣህ ፡ ዘንድ ፥ እርሱም ፡ ለአንተ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ለአባቶችህም ፡ ለአብርሃምና ፡ ለይስሐቅ ፡ ለያዕቆብም ፡ እንደ ፡ ማለ ፡ አምላክ ፡ ይሆንልህ ፡ ዘንድ ፥ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ዛሬ ፡ በሚያደርገው ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ትገባ ፡ ዘንድና ፡ የአምላክህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መሐላ ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

፲፬ እኔም ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ኪዳንና ፡ ይህን ፡ መሐላ ፡ የማደርገው ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፤ ፲፭ ነገር ፡ ግን ፡ ዛሬ ፡ በአምላካችን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ በዚህ ፡ ከሚቆም ፡ ሰው ፡ ጋር ፥ ዛሬም ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ በዚህ ፡ ከሌለ ፡ ሰው ፡ ጋር ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ፲፮ ነገር ፡ ግን ፡ እኛ ፡ በግብፅ ፡ ምድር ፡ እንደ ፡ ተቀመጥን ፡ በመካከላቸውም ፡ ባለፋችሁባቸው ፡ አሕዛብ ፡ መካከል ፡ ፲፯ እንዳለፍን ፡ አውቃችኋልና ፥ ርኩስነታቸውንም ፡ በእነርሱም ፡ ዘንድ ፡ የነበሩትን ፡ የእንጨ

ትና ፡ የድንጋይ ፡ የብርና ፡ የወርቅም ፡ ጣዖቶቻ
፲፰፡ ቸውን ፡ አይታችኋልና ፥ ሄዶ ፡ የእነዚያን ፡ አሕ
ዛብ ፡ አማልክት ፡ ያመልክ ፡ ዘንድ ፡ ከአምላኩ ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ልቡን ፡ ዛሬ ፡ የሚያስት ፡ ወንድ ፡
ወይም ፡ ሴት ፡ ወይም ፡ ወገን ፡ ወይም ፡ ነገድ ፡
አይኑርብችሁ ፤ ሐሞትና ፡ እሬትም ፡ የሚያበቅል ፡
፲፱፡ ሥር ፡ አይሁንብችሁ ። የዚህንም ፡ እርግማን ፡
ቃሎች ፡ የሰማ ፡ ሰው ፡— ምንም ፡ እንኳ ፡ በልቤ ፡
ደንዳንነት ፡ ብሄድ ፥ ለጥማቴም ፡ ስካር ፡ ብጨ
ምር ፥ ሰላም ፡ ይሆንልኛል ፡ ብሎ ፡ ሰውነቱን ፡
፳፡ በልቡ ፡ የሚባርክ ፡ ቢኖር ፥ የእግዚአብሔር ፡
ቍጣ ፡ ቅንዓቱም ፡ በዚያ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ይጤሳል ፡
እንጂ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቅርታ ፡ አያደርግለ
ትም ፤ በዚህም ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈው ፡ እርግ
ማን ፡ ሁሉ ፡ በላዩ ፡ ይኖራል ፥ እግዚአብሔርም ፡
፳፩፡ ስሙን ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡ ይደመስሰዋል ። እግ
ዚአብሔርም ፡ በዚህ ፡ ሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ እንደ ፡
ተጻፈው ፡ እንደ ፡ ቃል ፡ ኪዳኑ ፡ እርግማን ፡ ሁሉ ፡
ከእስራኤል ፡ ነገዶች ፡ ሁሉ ፡ ለጥፋት ፡ ይለየዋል ።
፳፪፡ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የሚነሣ ፡ ትውልድ ፡ ከእና
ንተም ፡ በኋላ ፡ የሚሆኑ ፡ ልጆቻችሁ ፡ ከሩቅ ፡
አገርም ፡ የሚመጣ ፡ እንግዳ ፥ የዚህን ፡ አገር ፡
መቅሠፍት ፥ እግዚአብሔርም ፡ በእርስዋ ፡ ያደ
፳፫፡ ረገውን ፡ ሥቃይዋን ፥ ምድርም ፡ በሁለንተናዋ ፡
ዲንና ፡ ጨው ፡ መቃጠልም ፡ እንደ ፡ ሆነባት ፥
እንዳትዘራም ፡ እንዳታበቅልም ፥ ማናቸውም ፡
ሣርና ፡ ልምላሜም ፡ እንዳይወጣባት ፥ እግዚ
አብሔር ፡ በቍጣውና ፡ በመዓቱ ፡ እንደ ፡ ገለባ
በጣቸው ፡ እንደ ፡ ሰዶምና ፡ ገሞራ ፡ እንደ ፡
አዳማና ፡ እንደ ፡ ሲባዮ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ በዩ ፡
፳፬፡ ጊዜ ፥ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡— እግዚአብሔር ፡ በዚ
ህች ፡ ምድር ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እንደዚህ ፡ አደ
ረገ ? ይህስ ፡ የቍጣው ፡ ታላቅ ፡ መቅሠፍት ፡
፳፭፡ ምንድር ፡ ነው ? ይላሉ ። ሰዎችም ፡ እንዲህ ፡
ይላሉ ፡— የአባቶቻቸው ፡ አምላክ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ በወጣቸው ፡ ጊዜ ፡ ከእ
ነርሱ ፡ ጋር ፡ ያደረገውን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ስለ ፡
፳፮፡ ተወ ፥ ሄደውም ፡ የማያውቋቸውንና ፡ ያልታ
ዘዙትን ፡ ሌሎችን ፡ አማልክት ፡ ስላመለኩና ፡
፳፯፡ ስለ ፡ ሰገዱላቸው ፥ ስለዚህ ፡ በዚህ ፡ መጽ
ሐፍ ፡ የተጻፈውን ፡ መርገም ፡ ሁሉ ፡ ያወርድ
ባት ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በዚህች ፡
፳፰፡ ምድር ፡ ነደደ ፤ ዛሬም ፡ እንዳለ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በቍጣና ፡ በመቅሠፍት ፡ በታላቅም ፡
መዓት ፡ ከምድራቸው ፡ ነቀላቸው ፥ ወደ ፡ ሌላም ፡
ምድር ፡ ጣላቸው ።
፳፱፡ ምሥጢሩ ፡ ለአምላካችን ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ነው ፤ የተገለጠው ፡ ግን ፡ የዚህን ፡ ሕግ ፡
ቃሎች ፡ ሁሉ ፡ እናደርግ ፡ ዘንድ ፡ ለእኛ ፡ ለዘላ
ለምም ፡ ለልጆቻችን ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

፩፡ እንዲህም ፡ ይሆናል ፤ እኔ ፡ በፊትህ ፡ ያኖር
ሁት ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፥ በረከቱና ፡ መርገሙ ፥
በወረደብህ ፡ ጊዜ ፥ አምላክህም ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በሚበትንህ ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡
፪፡ ሆነህ ፡ በልብህ ፡ በሰብኸው ፡ ጊዜ ፥ ወደ ፡ አም
ላክህም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተመልሰህ ፡ እኔ ፡
ዛሬ ፡ እንደማዝዝህ ፡ ሁሉ ፡ አንተና ፡ ልጆችህ ፡
በፍጹም ፡ ልብና ፡ በፍጹም ፡ ነፍስ ፡ ለቃሉ ፡ በታ
፫፡ ዘዝህ ፡ ጊዜ ፥ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምር
ከህን ፡ ይመልሳል ፡ ይራራልህማል ፤ አምላክ
ህም ፡ እግዚአብሔር ፡ አንተን ፡ ከበተነበት ፡ ከአ
ሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ መልሶ ፡ ይሰበስብሃል ።
፬፡ ሰዎችህም ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ፈል
ሰው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡
ከዚያ ፡ ይሰበስብሃል ፥ ከዚያም ፡ ያመጣሃል ።
፭፡ አባቶችህም ፡ ወደ ፡ ወረሱአት ፡ ምድር ፡ አም
ላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያገባሃል ፥ ትወርሳትማ
ለህ ፤ መልካምም ፡ ያደርግልሃል ፥ ከአባቶች
፮፡ ህም ፡ ይልቅ ፡ ያበዛሃል ። በሕይወትም ፡ እንድ
ትኖር ፥ አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ በፍጹም ፡
ልብህ ፡ በፍጹምም ፡ ነፍስህ ፡ እንድትወድድ ፡ አም
ላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልብህን ፡ የዘርህንም ፡
፯፡ ልብ ፡ ይገርዛል ። አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡
ይህችን ፡ መርገም ፡ ሁሉ ፡ በጠላቶችህና ፡ በሚ
ጠሉህ ፡ በሚያሳድዱህም ፡ ላይ ፡ ያመጣታል ።
፰፡ አንተም ፡ ተመልሰህ ፡ የአምላክህን ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ቃል ፡ ትሰማለህ ፥ ዛሬም ፡ እኔ ፡ የማ
፱፡፲፡ ዝዝህን ፡ ትእዛዙን ፡ ሁሉ ፡ ታደርጋለህ ። የአ
ምላክህንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ብትሰማ ፥
በዚህም ፡ ሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፉትን ፡ ትእዛ
ዙንና ፡ ሥርዓቱን ፡ ብትጠብቅ ፥ በፍጹምም ፡
ልብህ ፡ በፍጹምም ፡ ነፍስህ ፡ ወደ ፡ አምላክህ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ብትመለስ ፥ እግዚአብ
ሔር ፡ በአባቶችህ ፡ ደስ ፡ እንዳለው ፡ በመል
ካሙ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ በአንተ ፡ ደስ ፡
ይለዋልና ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእጅህ ፡
ሥራ ፡ ሁሉ ፡ በሆድህም ፡ ፍሬ ፡ በከብትህም ፡
ፍሬ ፡ በእርሻህም ፡ ፍሬ ፡ እጅግ ፡ ይባርክሃል ።
፲፩፡ እኔ ፡ ዛሬ ፡ የማዝዝህ ፡ ይህች ፡ ትእዛዝ ፡ ከባድ ፡
አይደለችም ፥ ከአንተም ፡ የራቀች ፡ አይደለ
፲፪፡ ችም ። ሰምተን ፡ እናደርጋት ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡
ወደ ፡ ሰማይ ፡ ወጥቶ ፡ እርስዋን ፡ የሚያመጣ
ልን ፡ ማን ፡ ነው ? እንዳትል ፡ በሰማይ ፡ አይደ
፲፫፡ ለችም ። ሰምተን ፡ እናደርጋት ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡
እኛ ፡ በሕሩን ፡ ተሻግሮ ፡ እርስዋን ፡ የሚያመጣ
ልን ፡ ማን ፡ ነው ? እንዳትል ፡ ከባሕሩ ፡ ማዶ ፡
፲፬፡ አይደለችም ። ነገር ፡ ግን ፡ ታደርገው ፡ ዘንድ ፡
ቃሉ ፡ በአፍህና ፡ በልብህ ፡ ውስጥ ፡ ለአንተ ፡
እጅግ ፡ ቅርብ ፡ ነው ።
፲፭፡ ተመልከት ፤ ዛሬ ፡ በፊትህ ፡ ሕይወትንና ፡
መልካምነትን ፥ ሞትንና ፡ ክፋትን ፡ አኑሬአ
፲፮፡ ለሁ ። በሕይወትም ፡ እንድትኖር ፡ እንድትበ
ዛም ፥ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ልትወር
ሳት ፡ በምትገባበት ፡ ምድር ፡ እንዲባርክህ ፥
አምላክህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትወድድ ፡ ዘንድ ፥
በመንገዱም ፡ ትሄድ ፡ ዘንድ ፡ ትእዛዙንና ፡ ሥር

ዓቱን ፡ ፍርዱንም ፡ ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ዛሬ ፡ እኔ ፡
፲፯ አዝዝሃለሁ ። ልብህ ፡ ግን ፡ ቢስት ፡ አንተም ፡
በትሰማ ፥ ብትታለልም ፥ ለሌሎችም ፡ አማል
፲፰ ክት ፡ ብትሰግድ ፡ ብታመልካቸውም ፥ ፈጽማ
ችሁ ፡ እንድትጠፉ ፡ እኔ ፡ ዛሬ ፡ እነግራችኋለሁ ፤
ዮርዳኖስን ፡ ተሻግረህ ፡ ትወርሳት ፡ ዘንድ ፡ በም
ትገባበት ፡ ምድር ፡ ዘመናችሁን ፡ አታስረዝ
፲፱ ሙም ። በፊታችሁ ፡ ሕይወትንና ፡ ሞትን ፡ በረ
ከትንና ፡ መርገምን ፡ እንዳስቀመጥሁ ፡ እኔ ፡ ዛሬ ፡
ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ አስመሰክ
ራለሁ ፤ እንግዲህ ፡ አንተና ፡ ዘርህ ፡ በሕይወት ፡
፳ ትኖሩ ፡ ዘንድ ፡ ሕይወትን ፡ ምረጥ ፤ እግዚአብ
ሔርም ፡ ለአባቶችህ ፡ ለአብርሃምና ፡ ለይስሐቅ ፡
ለያዕቆብም ፡ እንዲሰጣቸው ፡ በማለላቸው ፡ በም
ድሪቱ ፡ ትቀመጥ ፡ ዘንድ ፥ እርሱ ፡ ሕይወትህ ፡
የዘመንህም ፡ ርዝመት ፡ ነውና ፡ አምላክህን ፡
እግዚአብሔርን ፡ ትወድደው ፡ ትጠባበቀውም ፡
ቃሉንም ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡ ምረጥ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፩ ።

፩ ሙሴም ፡ ሄዶ ፡ ይህንን ፡ ቃል ፡ ለእስራኤል ፡
፪ ሁሉ ፡ ነገረ ። አላቸውም ፡— እኔ ፡ ዛሬ ፡ መቶ ፡
ሀያ ፡ ዓመት ፡ ሆኖኛል ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እወጣና ፡
እገባ ፡ ዘንድ ፡ አልችልም ፤ እግዚአብሔርም ፡—
ይህን ፡ ዮርዳኖስን ፡ አትሻገርም ፡ ብሎኛል ።
፫ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እርሱ ፡ በፊትህ ፡
ያልፋል ፤ እርሱ ፡ እነዚህን ፡ አሕዛብ ፡ ከፊትህ ፡
ያጠፋቸዋል ፡ ትወርሳቸውማለህ ፤ እግዚአብሔ
ርም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ኢያሱ ፡ በፊትህ ፡ ይሻገ
፬ ራል ። እግዚአብሔርም ፡ ባጠፋቸው ፡ በአሞ
ራውያን ፡ ነገሥታት ፡ በሴዎንና ፡ በዐግ ፡ በም
፭ ድራቸውም ፡ እንዳደረገ ፡ ያደርግባቸዋል ። እግ
ዚአብሔርም ፡ በፊታችሁ ፡ አሳልፎ ፡ ይጥላቸ
ዋል ፥ እንዳዘዝኋችሁም ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ታደ
፮ ርጉባቸዋላችሁ ። ጽኑ ፥ አይዞአችሁ ፥ አት
ፍሩ ፥ ከፊታቸውም ፡ አትደንግጡ ፤ አምላክህ ፡
እግዚአብሔር ፡ እርሱ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይሄ
፯ ዳል ፤ አይጥልህም ፥ አይተውህም ። ሙሴም ፡
ኢያሱን ፡ ጠርቶ ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡—
አንተ ፡ ከዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ጋር ፡ እግዚአብሔር ፡
ለአባቶቻቸው ፡ እንዲሰጥ ፡ ወደ ፡ ማለላቸው ፡
ምድር ፡ ትገባለህና ፥ እርስዋንም ፡ ለእነርሱ ፡ ታወ
፰ ርሳለህና ፡ ጽና ፥ አይዞህ ። በፊትህም ፡ የሚሄድ ፡
እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ፤ ከአንተ ፡ ጋር ፡
ይሆናል ፥ አይጥልህም ፥ አይተውህም ፤ አት
ፍራ ፥ አትደንግጥ ፡ አለው ።
፱ ሙሴም ፡ ይህችን ፡ ሕግ ፡ ጻፈ ፥ የእግዚአብ
ሔርንም ፡ የቃል ፡ ኪዳኑን ፡ ታቦት ፡ ይሸከሙ ፡
ለነበሩት ፡ ለሌዊ ፡ ልጆች ፡ ለካህናቱ ፡ ለእስራ
፲ ኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሁሉ ፡ ሰጣት ። ሙሴም ፡
እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ፡— በሰባተኛው ፡
ዓመት ፡ መጨረሻ ፥ በዕዳ ፡ ምሕረት ፡ ዘመን ፥
፲፩ በዳስ ፡ በዓል ፥ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ በአምላክህ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይታይ ፡ ዘንድ ፡ እርሱ ፡
በመረጠው ፡ ስፍራ ፡ ሲከማች ፥ ይህን ፡ ሕግ ፡ በእ
ስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ በጆሮው ፡ አንብበው ።
፲፪ ይሰሙና ፡ ይማሩ ፡ ዘንድ ፥ አምላካችሁንም ፡
እግዚአብሔርን ፡ ይፈሩ ፡ ዘንድ ፥ የዚህንም ፡
ሕግ ፡ ቃሎች ፡ ሁሉ ፡ ጠብቀው ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡
ሕዝቡን ፡ ወንዶችንና ፡ ሴቶችን ፡ ሕፃናቶች
ንም ፡ በአገራችሁ ፡ ደጅ ፡ ያለውንም ፡ መጻተኛ ፡
፲፫ ሰብስብ ። የሕግን ፡ ቃላት ፡ የማያውቁ ፡ ልጆቻ
ቸውም ፡ ዮርዳኖስን ፡ ተሻግራችሁ ፡ ልትወርሱ
አት ፡ በምትሄዱባት ፡ ምድር ፡ በምትኖሩበት ፡
ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ይስሙ ፥ አምላካችሁን ፡ እግዚ
አብሔርንም ፡ መፍራት ፡ ይማሩ ።
፲፬ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡— የምትሞትበት ፡
ቀን ፥ እነሆ ፥ ቀረበ ፤ ኢያሱን ፡ ጠርተህ ፡ እርሱን ፡
አዝዘው ፡ ዘንድ ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡
ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ቁም ፡ አለው ። ሙሴና ፡ ኢያ
ሱም ፡ ሄደው ፡ በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡
፲፭ ቆሙ ። እግዚአብሔርም ፡ በድንኳኑ ፡ ውስጥ ፡
በደመና ፡ ዓምድ ፡ ተገለጠ ፤ የደመናውም ፡
፲፮ ዓምድ ፡ በድንኳኑ ፡ ደጃፍ ፡ ላይ ፡ ቆመ ። እግ
ዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ አለው ፡— እነሆ ፥ ከአ
ባቶችህ ፡ ጋር ፡ ትተኛለህ ፤ ይህም ፡ ሕዝብ ፡ ይነ
ሣል ፥ ይቀመጥባትም ፡ ዘንድ ፡ በሚሄድባት ፡
ምድር ፡ መካከል ፡ ያሉትን ፡ ሌሎችን ፡ አማል
ክት ፡ ተከትሎ ፡ ያመነዝራል ፥ እኔንም ፡ ይተወ
ኛል ፥ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ያደረግሁትን ፡ ቃል ፡
፲፯ ኪዳን ፡ ያፈርሳሉ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ቍጣዬ ፡
ይነድድባቸዋል ፥ እተዋቸውማለሁ ፥ ፊቴንም ፡
እሰውርባቸዋለሁ ፥ ለአሕዛብም ፡ መብል ፡ ይሆ
ናሉ ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡— በእውነት ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በእኛ ፡ መካከል ፡ የለምና ፡ ይህ ፡ ክፉ ፡
ነገር ፡ ሁሉ ፡ አገኘን ፡ እስኪሉ ፡ ድረስ ፡ ብዙ ፡
፲፰ ክፉ ፡ ነገርና ፡ ጭንቀት ፡ ይደርስባቸዋል ። ሌሎ
ችን ፡ አማልክት ፡ ተከትለዋልና ፡ ስላደረጉት ፡
ክፋት ፡ ሁሉ ፡ እኔ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ፈጽሜ ፡ ፊቴን ፡
፲፱ እሰውራለሁ ። አሁንም ፡ ይህችን ፡ መዝሙር ፡
ለእናንተ ፡ ጻፉ ፥ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ አስ
ተምሩአቸው ፤ ይህችም ፡ መዝሙር ፡ በእስራ
ኤል ፡ ላይ ፡ ምስክር ፡ ትሆንልኝ ፡ ዘንድ ፡ በአፋ
፳ ቸው ፡ አድርጓት ። ለአባቶቻቸው ፡ ወደ ፡ ማል
ሁላቸው ፥ ወተትና ፡ ማር ፡ ወደምታፈስሰው ፡
ምድር ፡ ካገባኋቸው ፡ በኋላ ፥ ከበሉም ፡ ከጠገ
ቡም ፡ ከደነደኑም ፡ በኋላ ፥ ሌሎችን ፡ አማልክት ፡
ተከትለው ፡ ያመልካሉ ፥ እኔንም ፡ ይንቃሉ ፥
፳፩ ቃል ፡ ኪዳኔንም ፡ ያፈርሳሉ ። ዛሬ ፡ ወደ ፡ ማል
ሁላቸው ፡ ምድር ፡ ገና ፡ ሳላገባቸው ፡ የሚያስ
ቡትን ፡ አሳብ ፡ አውቃለሁና ፥ ከልጆቻቸውም ፡
አፍ ፡ አትረሳምና ፡ ብዙ ፡ ክፉ ፡ ነገርና ፡ ጭን
ቀት ፡ በደረሰባቸው ፡ ጊዜ ፡ ይህች ፡ መዝሙር ፡
ምስክር ፡ ሆና ፡ በፊታቸው ፡ ትመሰክራለች ።
፳፪ ሙሴም ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ይህችን ፡ መዝሙር ፡
ጻፈ ፥ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ አስተማራት ።
፳፫ የነዌንም ፡ ልጅ ፡ ኢያሱን ፡— የእስራኤልን ፡
ልጆች ፡ ወደ ፡ ማልሁላቸው ፡ ምድር ፡ ታገባለ

ሁና ፡ ጽና ፥ አይዞህ ፤ እኔም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ እሆናለሁ ፡ ብሎ ፡ አዘዘው ።

፳፬ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ሙሴ ፡ የዚህን ፡ ሕግ ፡ ቃሎች ፡ በመጽሐፍ ፡ ከጻፈ ፡ ከፈጸመም ፡ በኋላ ፥ ፳፭ ሙሴ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ የሚሸከሙትን ፡ ሌዋውያንን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፳፮ አዘዘ ፡— ይህን ፡ የሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ ውሰዱ ፥ በዚያም ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ምስክር ፡ እንዲሆን ፡ በአምላካችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ፳፯ ታቦት ፡ አጠገብ ፡ አኑሩት ። እኔ ፡ ዓመፃችሁንና ፡ የአንገታችሁን ፡ ድንዳኔ ፡ አውቃለሁና ፤ እኔም ፡ ዛሬ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ገና ፡ በሕይወት ፡ ሳለሁ ፡ እናንተ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ዐምፃችኋል ፤ ይልቁንስ ፡ ከሞትሁ ፡ በኋላ ፡ እንዴት ፡ ፳፰ ይሆናል ? ይህን ፡ ቃል ፡ በጆሮአቸው ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፥ ሰማይንና ፡ ምድርንም ፡ አስመሰክርባቸው ፡ ዘንድ ፡ የነገዶቻችሁን ፡ ሽማግሌዎች ፡ ፳፱ ሁሉ ፡ አለቆቻችሁንም ፡ ሰብስቡልኝ ፤ ከሞትሁ ፡ በኋላ ፡ ፈጽማችሁ ፡ እንድትረክሱ ፥ ካዘዝኋችሁም ፡ መንገድ ፡ ፈቀቅ ፡ እንድትሉ ፡ አውቃለሁና ። በእጃችሁም ፡ ሥራ ፡ ታስቈጡት ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ስላደረጋችሁ ፡ በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ያገኛችኋል ።

፴ ሙሴም ፡ በእስራኤል ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ ጆሮ ፡ የዚህች ፡ መዝሙር ፡ ቃሎች ፡ እስኪፈጸሙ ፡ ድረስ ፡ ተናገረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

፩ ሰማያት ፡ ሆይ ፥ አድምጡ ፥ እኔም ፡ እናገራለሁ ፤
ምድርም ፡ የአፌን ፡ ቃሎች ፡ ትስማ ።
፪ ትምህርቴ ፡ እንደ ፡ ዝናብ ፡ ትፈስሳለች ፥
ነገሬ ፡ እንደ ፡ ጠል ፡ ትንጠባጠባለች ፤
በልምላሜ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ጤዛ ፥
በሣርም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ካፊያ ።
፫ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ እጠራለሁና ፤
ለአምላካችን ፡ ታላቅነትን ፡ ስጡ ።
፬ እርሱ ፡ አምላክ ፡ ነው ፤ ሥራውም ፡ ፍጹም ፡ ነው ፤
መንገዱም ፡ ሁሉ ፡ የቀና ፡ ነው ፤
የታመነ ፡ አምላክ ፥ ክፋትም ፡ የሌለበት ፥
እርሱ ፡ እውነተኛና ፡ ቅን ፡ ነው ።
፭ እነርሱ ፡ ረከሱ ፤ ልጆቹም ፡ አይደሉም ፤
ነውርም ፡ አለባቸው ፤ ጠማማና ፡ ገልበጥባጣ ፡ ትውልድ ፡ ናቸው ።
፮ ደንቆሮ ፡ ብልሃተኛም ፡ ያልሆንህ ፡ ሕዝብ ፡ ሆይ ፥
ለእግዚአብሔር ፡ ይህንን ፡ ትመልሳለህ ?
የገዛህ ፡ አባትህ ፡ አይደለምን ?
የፈጠረህና ፡ ያጸናህ ፡ እርሱ ፡ ነው ።
፯ የዱሮውን ፡ ዘመን ፡ አስብ ፥
የብዙ ፡ ትውልድንም ፡ ዓመታት ፡ አስተውል ፤
አባትህን ፡ ጠይቅ ፥ ያስታውቅህማል ፤
ሽማግሌዎችህን ፡ ጠይቅ ፥ ይነግሩህማል ።
፰ ልዑል ፡ ለአሕዛብ ፡ ርስታቸውን ፡ በወረሰ ፡ ጊዜ ፥
የአዳምን ፡ ልጆች ፡ በለየ ፡ ጊዜ ፥
እንደ ፡ እስራኤል ፡ ልጆች ፡ ቍጥር ፡
የአሕዛብን ፡ ድንበር ፡ አቆመ ።
፱ የእግዚአብሔር ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ ሕዝቡ ፡ ነው ፤
ያዕቆብም ፡ የርስቱ ፡ ገመድ ፡ ነው ።
፲ በምድረ ፡ በዳ ፡ በጥማት ፥
የነፋስ ፡ ጩኸትም ፡ በሞላበት ፡ ውድማ ፡ አገኘው ፤
ከበበው ፡ ተጠነቀቀለትም ፤
እንደ ፡ ዓይን ፡ ብሌን ፡ ጠበቀው ።
፲፩ ንስር ፡ ጫጩቶቹን ፡ እንደሚያወጣ ፥
በእነርሱም ፡ ላይ ፡ እንደሚሰፍፍ ፥
ክንፎቹን ፡ ዘርግቶ ፡ ወሰዳቸው ፥
በክንፎቹም ፡ አዘላቸው ።
፲፪ እግዚአብሔር ፡ ብቻውን ፡ መራው ፤
ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ሌላ ፡ አምላክ ፡ አልነበረም ።
፲፫ በምድር ፡ ከፍታ ፡ ላይ ፡ አወጣው ፤
የእርሻውን ፡ ፍሬ ፡ በላ ፤
ከዓለትም ፡ ድንጋይ ፡ በሚገኝ ፡ ማር ፥
ከጭንጫውም ፡ ድንጋይ ፡ በሚገኝ ፡ ዘይት ፡ አጠባው ፤
፲፬ የላሙንም ፡ ቅቤ ፥ የመንጋውንም ፡ ወተት ፥
ከጠቦት ፡ ስብ ፡ ጋር ፥
የባሳንንም ፡ አውራ ፡ በግ ፥ ፍየሉንም ፥
ከስንዴ ፡ እሸት ፡ ጋር ፡ በላህ ፤
ከወይኑም ፡ ደም ፡ ያለውን ፡ ጠጅ ፡ ጠጣህ ።
፲፭ ይሹሩን ፡ ወፈረ ፥ ረገጠ ፤
ወፈረ ፥ ደነደነ ፥ ሰባ ፤
የፈጠረውንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተወ ፤
የመድኃኒቱንም ፡ አምላክ ፡ ናቀ ።
፲፮ በሌሎች ፡ አማልክት ፡ አስቀኑት ፥
በርኵሰታቸውም ፡ አስቈጡት ።
፲፯ እግዚአብሔር ፡ ላልሆኑ ፡ አጋንንት ፥
ለማያውቋቸውም ፡ አማልክት ፥
በቅርብ ፡ ጊዜ ፡ ለተነሡ ፡ ለአዲሶች ፡
አባቶቻቸውም ፡ ላልፈሩአቸው ፡ አማልክት ፡ ሠዉ ።
፲፰ የወለደህን ፡ አምላክ ፡ ተውህ ፥
ያሳደገህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ረሳህ ።
፲፱ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆችም ፡ ስላስቈጡት ፡
እግዚአብሔር ፡ አይቶ ፡ ጣላቸው ።
፳ እርሱም ፡ አለ ፡— ፊቴን ፡ እሰውርባቸዋለሁ ፤
ፍጻሜያቸው ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አያለሁ ፤
ጠማማ ፡ ትውልድ ፥
ያልታመኑም ፡ ልጆች ፡ ናቸው ።
፳፩ አምላክ ፡ በልሆነው ፡ አስቀኑኝ ፤

ቍ ፲፭ ፤ በዕብራይስጥ ፡ ይሹሩን ፡ የሚለውን ፡ ግዕዙ ፡ ያዕቆብ ፡ ይለዋል ።

በምናምንቴዎቻቸውም ፡ አስቈጡኝ ፤
እኔም ፡ ሕዝብ ፡ ባልሆነው ፡ አስቀናቸዋለሁ ፤
በማያስተውል ፡ ሕዝብ ፡ አስቈጣቸዋለሁ ።
፳፪ ፤ እሳት ፡ ከቍጣዬ ፡ ትነድዳለችና ፥
እስከ ፡ ሲኦል ፡ ድረስ ፡ ታቃጥላለች ፥
ምድርንም ፡ ከፍሬዋ ፡ ጋር ፡ ትበላለች ፥
የተራሮችን ፡ መሠረት ፡ ታነድዳለች ።
፳፫ ፤ መከራን ፡ እጨምርባቸዋለሁ ፤
በፍላጻቼም ፡ እወጋቸዋለሁ ።
፳፬ ፤ በራብ ፡ በንዳድ ፡ ይጠፋሉ ፤
በንዳድና ፡ በመራራ ፡ ጥፋት ፡ ያልቃሉ ፤
የአራዊትን ፡ ጥርስ ፥
የምድርንም ፡ እባብ ፡ መርዝ ፡ እሰድድባቸዋለሁ ።
፳፭ ፤ ጕልማሳውን ፡ ከድንግል ፥ ሕፃኑንም ፡ ከሽማግሌ ፡ ጋር ፥
በሜዳ ፡ ሰይፍ ፥ በቤትም ፡ ውስጥ ፡ ድንጋጤ ፡ ያጠፋቸዋል ።
፳፮ ፤ እበትናቸዋለሁ ፡ አልሁ ፤
ከሰዎችም ፡ መካከል ፡ መታሰቢያቸውን ፡ አጠፋለሁ ።
፳፯ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ጠላቶቻቸው ፡ እንዳይታበዩ ፡—
እጃችን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለች ፡ እንጂ ፡
እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ አላደረገም ፡ እንዳይሉ ፥
ስለ ፡ ጠላቱ ፡ ቍጣ ፡ ፈራሁ ።
፳፰ ፤ ምክር ፡ ያጡ ፡ ሕዝብ ፡ ናቸው ፥
ማስተዋልም ፡ የላቸውም ።
፳፱ ፤ አእምሮ ፡ ቢኖራቸው ፥
ይህንን ፡ ያስተውሉ ፡ ነበር ፥
ፍጻሜያቸውንም ፡ ያስቡ ፡ ነበር ።
፴ ፤ እርሱ ፡ አምላካቸው ፡ ካልሸጣቸው ፥
እግዚአብሔርም ፡ አሳልፎ ፡ ካልሰጣቸው ፥
አንድ ፡ ሰው ፡ እንዴት ፡ ሺህን ፡ ያሳድድ ፡ ነበር ?
ሁለቱስ ፡ እንዴት ፡ አሥሩን ፡ ሺህ ፡ ያሸሹ ፡ ነበር ?
፴፩ ፤ አምላካችን ፡ እንደ ፡ አማልክቶቻቸው ፡ አይደለም ፤
ጠላቶቻችንም ፡ ሰነፎች ፡ ናቸው ።
፴፪ ፤ ወይናቸው ፡ ከሰዶም ፡ ወይን ፥
ከገሞራም ፡ እርሻ ፡ ነው ፤
ፍሬያቸው ፡ ሐሞት ፡ ነው ፤
ዘለላውም ፡ መራራ ፡ ነው ።
፴፫ ፤ የወይን ፡ ጠጃቸው ፡ የእባብ ፡ መርዝ ፥
የእፉኝትም ፡ ሥራይ ፡ ነው ።
፴፬ ፤ ይህ ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ተጠብቆ ፡ የለምን ?
በመዝገቤስ ፡ የታተመ ፡ አይደለምን ?
፴፭ ፤ የጥፋታቸው ፡ ቀን ፡ ቀርቦአልና ፥
የሚመጣባቸውም ፡ ነገር ፡ ይፈጥናልና ፡
እግራቸው ፡ ሲሰናከል ፡
በቀልና ፡ ፍርድ ፡ የእኔ ፡ ነው ።
፴፮ ፤ ኀይላቸውም ፡ እንደ ፡ ደከመ ፥
የተዘጋ ፡ የተለቀቀም ፡ እንደሌለ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡
እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ፡ ይፈርዳል ፥
ስለ ፡ ባሪያዎቹም ፡ ያዝናል ።
፴፯ ፤ እርሱም ፡ ይላል ፡— አማልክቶቻቸው ፡ የት ፡ ናቸው ?
ይታመኑባቸው ፡ የነበሩት ፡ አማልክት ?
፴፰ ፤ የመሥዋዕታቸውን ፡ ስብ ፡ የበሉ ፥
የመጠጥ ፡ ቍርባናቸውንም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ የጠጡ ?
እነርሱ ፡ ይነሡ ፥ ይርዱአችሁም ፥
መጠጊያም ፡ ይሁኑላችሁ ።
፴፱ ፤ አሁንም ፡ እኔ ፡ ብቻዬን ፡ እኔ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፥
ከእኔም ፡ በቀር ፡ አምላክ ፡ እንደሌለ ፡ እዩ ፤
እኔ ፡ እገድላለሁ ፥ አድንማለሁ ፤
እኔ ፡ እመታለሁ ፥ እፈውስማለሁ ፤
ከእጄም ፡ የሚያድን ፡ የለም ።
፵ ፤ እጄን ፡ ወደ ፡ሰማይ ፡ እዘረጋለሁና ፥
እንዲህም ፡ እላለሁ ፡— ለዘላለም ፡ እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡
፵፩ ፤ የሚንበገበግ ፡ ሰይፌን ፡ እስለዋለሁ ፥
እጄም ፡ ፍርድን ፡ ትይዛለች ፥
ጠላቶቼንም ፡ እበቀላለሁ ፥
ለሚጠሉኝም ፡ ፍዳቸውን ፡ እከፍላለሁ ።
፵፪ ፤ ከተወጉት ፡ ከተማረኩትም ፡ ደም ፥
ፍላጻቼን ፡ በደም ፡ አሰክራለሁ ፤
ከጠላት ፡ አለቆችም ፡ ራስ ፡
ሰይፌ ፡ ሥጋ ፡ ይበላል ።
፵፫ ፤ የባሪያዎቹን ፡ ደም ፡ ይበቀላልና ፥
ጠላቶቹንም ፡ ይበቀላቸዋልና ፥
ምድሪቱንና ፡ ሕዝቡን ፡ ይክሳልና ፡
እናንተ ፡ አሕዛብ ፡ ሆይ ፥ ከሕዝቡ ፡ ጋር ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ።

፵፬ ፤ ሙሴም ፡ የነዌም ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡ የዚህችን ፡ መዝሙር ፡ ቃሎች ፡ ሁሉ ፡ በሕዝቡ ፡ ጆሮ ፡ ተናገሩ ። ፵፭ ፤ ሙሴም ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ተናግሮ ፡ ፈጸመ ። ፵፮ ፤ እርሱም ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— የዚህን ፡ ሕግ ፡ ቃሎች ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቁና ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ልጆቻችሁን ፡ እንድታዝዙበት ፡ ዛሬ ፡ የምመሰክርላችሁን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ በልባችሁ ፡ አኑሩት ። ፵፯ ፤ ይህ ፡ ነገር ፡ ሕይወታችሁ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ለእናንተ ፡ ከንቱ ፡ አይደለምና ፤ በዚህም ፡ ነገር ፡ ትወርሱአት ፡ ዘንድ ፡ ዮርዳኖስን ፡ ተሻግራችሁ ፡ በምትገቡባት ፡ ምድር ፡ ረጅም ፡ ዘመን ፡ ትቀመጣላችሁ ።

፵፰ ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ፵፱ ፤ ወደዚህ ፡ በኢያሪኮ ፡ አንጻር ፡ በሞዓብ ፡ ምድር ፡ በዓባሪም ፡ ተራራ ፡ ውስጥ ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ ናባው ፡ ተራራ ፡ ውጣ ፥ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡ አድርጌ ፡ የምሰጣቸውን ፡ የከነዓንን ፡ ምድር ፡ እይ ፤ ፶ ፤ ወንድምህም ፡ አሮን ፡ በሖር ፡ ተራራ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ወደ ፡ ወገኖቹም ፡ እንደ ፡ ተከማቸ ፥ በወጣህበት ፡ ተራራ ፡ ሙት ፥ ወደ ፡ ወገኖችህም ፡ ተከማች ፤ ፶፩ ፤ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ በጺን ፡

ምድረ ፡ በዳ ፡ በቃዴስ ፡ ባለው ፡ በመሪባ ፡ ውኃ ፡
ስለ ፡ በደላችሁኝ ÷ በእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
፶፪ መካከል ፡ ስላልቀደሳችሁኝ ÷ ምድሪቱን ፡ ፊት ፡
ለፊት ፡ ታያለህ ፡ እንጂ ፡ ወደዚያች ፡ እኔ ፡ ለእ
ስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወደምሰጣቸው ፡ ምድር ፡
አትገባም ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፫ ።

፩ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ሙሴ ፡ ሳይሞት ፡
የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ የባረከባት ፡ በረከት ፡
፪ ይህች ፡ ናት ። እንዲህም ፡ አለ ፡—
እግዚአብሔር ፡ ከሲና ፡ መጣ ÷
በሴይርም ፡ ተገለጠ ፤
ከፋራን ፡ ተራራ ፡ አበራላቸው ÷
ከአእላፋትም ፡ ቅዱሳኑ ፡ መጣ ፤
በስተ ፡ ቀኙም ፡ የእሳት ፡ ሕግ ፡ ነበረላቸው ።
፫ ሕዝቡንም ፡ ወደዳቸው ፤
ቅዱሳኑ ፡ ሁሉ ፡ በእጅህ ፡ ናቸው ፤
በእግሮችህም ፡ አጠገብ ፡ ተቀመጡ ፤
ቃሎችህን ፡ ይቀበላሉ ።
፬ ሙሴ ፡ ለያዕቆብ ፡ ጉባኤ ፡ ርስት ፡ የሆነውን ፡
ሕግ ፡ አዘዘን ።
፭ የሕዝቡ ፡ አለቆች ፡ ከእስራኤል ፡ ነገዶች ፡
ሁሉ ፡ ጋር ፡ በተከማቹ ፡ ጊዜ ÷
ንጉሥ ፡ በይሹሩን ፡ ነበረ ።
፮ ሮቤል ፡ በሕይወት ፡ ይኑር ÷ አይሙት ፤
ሰዎቹም ፡ በቍጥር ፡ ብዙ ፡ ይሁኑ ።
፯ የይሁዳ ፡ በረከት ፡ ይህ ፡ ነው ፤ እንዲህም ፡ አለ ፡—
አቤቱ ÷ የይሁዳን ፡ ድምፅ ፡ ስማ ÷
ወደ ፡ ወገኖቹም ፡ አግባው ፤
እጆቹ ፡ ይጠንክሩለት ፤
በጠላቶቹ ፡ ላይ ፡ ረዳት ፡ ትሆነዋለህ ።
፰ ስለ ፡ ሌዊም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—
ቱሚምህና ፡ ኡሪምህ ፡ ለቅዱስህ ፡ ሰው ፡
ነው ÷
በማሳህ ፡ ለፈተንኸው ÷
በመሪባ ፡ ውኃም ፡ ለተከራከርኸው ÷
፱ ስለ ፡ አባቱና ፡ ስለ ፡ እናቱ ፡— አላየሁም ፡
ላለ ÷
ወንድሞቹንም ፡ ላላስተዋለ ÷
ልጆቹንም ፡ ላላወቀ ፤
ቃልህን ፡ አደረጉ ÷
ቃል ፡ ኪዳንህንም ፡ ጠበቁ ።
፲ ፍርድህን ፡ ለያዕቆብ ÷
ሕግህንም ፡ ለእስራኤል ፡ ያስተምራሉ ፤
በፊትህ ፡ ዕጣንን ÷
በመሠዊያህም ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡
ይሠዋሉ ።
፲፩ አቤቱ ÷ ሀብቱን ፡ ባርክ ÷
የእጁንም ፡ ሥራ ፡ ተቀበል ፤
የሚነሣበትን ፡ ወገብ ፡ ውጋው ÷
የሚጠሉትም ፡ አይነሡ ።
፲፪ ስለ ፡ ብንያምም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—
በእግዚአብሔር ፡ የተወደደ ፡ በእርሱ ፡
ዘንድ ፡ ተማምኖ ፡ ይኖራል ፤
ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ይጋርደዋል ÷
በትከሻውም ፡ መካከል ፡ ያድራል ።
፲፫ ስለ ፡ ዮሴፍም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—
ምድሩ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተባረከ ፡
ይሁን ፤
በሰማያት ፡ ገናንነት ፡ በጠል ÷
በታችኛውም ፡ ቀላይ ÷
፲፬ በፀሐዩ ፡ ፍሬያት ፡ ገናንነት ÷
በጨረቃውም ፡ መውጣት ፡ ገናንነት ÷
፲፭ በቀደሙትም ፡ ተራሮች ፡ ከፍተኛነት ÷
በዘላለሙም ፡ ኮረብቶች ፡ ገናንነት ÷
፲፮ በምድሪቱም ፡ ገናንነትና ፡ ሞላዋ ÷
በቍጥቋጦው ፡ ውስጥ ፡ ከነበረው ፡ በረከት ፡
በዮሴፍ ፡ ራስ ፡ ላይ ÷
ከወንድሞቹም ፡ በተለየው ፡ ራስ ፡ አናት ፡
ላይ ፡ ይውረድ ።
፲፯ ለላሞች ፡ በኵር ፡ ግርማ ፡ ይሆናል ፤
ቀንዶቹ ፡ አንድ ፡ ቀንድ ፡ እንዳለው ፡ ናቸው ፤
በእነርሱ ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ያሉትን ፡
አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ይወጋል ፤
የኤፍሬም ፡ እልፍ ፡ አእላፋት ÷
የምናሴም ፡ አእላፋት ፡ እነርሱ ፡ ናቸው ።
፲፰ ስለ ፡ ዛብሎንም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—
ዛብሎን ፡ ሆይ ÷ በመውጣትህ ÷
ይሳኮር ፡ ሆይ ÷ በድንኳንህ ፡ ውስጥ ፡ ደስ ፡
ይበላችሁ ።
፲፱ የተሰወረውን ፡ የአሸዋውን ፡ መዝገብ ÷
የባሕሩንም ፡ ባለጠግነት ፡ ይጠባሉና ፡
አሕዛብን ፡ ወደ ፡ ተራራው ፡ ይጠራሉ ፤
በዚያ ፡ የጽድቅ ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዋሉ ።
፳ ስለ ፡ ጋድም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—
ጋድን ፡ ሰፊ ፡ ያደረገ ፡ ቡሩክ ፡ ይሁን ፤
እንደ ፡ አንበሳይቱ ፡ ዐርፎአል ፤
ክንድንና ፡ ራስን ፡ ይቀጠቅጣል ።
፳፩ በዚያ ፡ የአለቃ ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ ቀርቶአልና ፡
የመጀመሪያውን ፡ ክፍል ፡ ለራሱ ፡ መረጠ ፤
ወደ ፡ ሕዝብ ፡ አለቆችም ፡ መጣ ፤
የእግዚአብሔርንም ፡ ጽድቅ ÷
ፍርዱንም ፡ ከእስራኤል ፡ ጋር ፡ አደረገ ።
፳፪ ስለ ፡ ዳንም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—
ዳን ፡ የአንበሳ ፡ ደቦል ፡ ነው ፤
ከባሳን ፡ ዘልሎ ፡ ይወጣል ።
፳፫ ስለ ፡ ንፍታሌምም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—
ንፍታሌም ፡ በሞገስ ፡ ጠግቦአል ÷
የእግዚአብሔርንም ፡ በረከት ፡ ተሞልቶ
አል ፤
ባሕሩንና ፡ ደቡቡን ፡ ይወርሳል ።
፳፬ ስለ ፡ አሴርም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—
አሴር ፡ በልጆች ፡ የተባረከ ፡ ይሁን ፤
በወንድሞቹ ፡ የተወደደ ፡ ይሁን ፤
እግሩንም ፡ በዘይት ፡ ውስጥ ፡ ያጥልቅ ።
፳፭ ጫማህ ፡ ብረትና ፡ ናስ ፡ ይሆናል ፤
እንደ ፡ ዕድሜህ ፡ እንዲሁ ፡ ኃይልህ ፡ ይሆናል ።

፳፮ ይሹሩን ፡ ሆይ ÷ በሰማያት ፡ ላይ ፡ ለረድ
ኤትህ ÷
በደመናትም ፡ ላይ ፡ በታላቅነት ፡ እንደሚ
ሄድ ፡
እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያለ ፡ ማንም ፡ የለም ።
፳፯ መኖሪያህ ፡ የዘላለም ፡ አምላክ ፡ ነው ÷
የዘላለምም ፡ ክንዶች ፡ ከአንተ ፡ በታች ፡
ናቸው ፤
ጠላትህን ፡ ከፊትህ ፡ አውጥቶ ፦
አጥፋው ፡ ይላል ።
፳፰ እስራኤልም ፡ ተማምኖ ÷
የያዕቆብም ፡ ምንጭ ፡ ብቻውን ÷
እህልና ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ባለባት ፡ ምድር ፡
ይኖራል ፤
ሰማያቱም ፡ ጠልን ፡ ያንጠባጥባሉ ።
፳፱ እስራኤል ፡ ሆይ ÷ ምስጉን ፡ ነህ ፤
በእግዚአብሔር ፡ የዳነ ፡ ሕዝብ ፡ እንደ ፡
አንተ ፡ ማን ፡ ነው ?
እርሱ ፡ የረድኤትህ ፡ ጋሻ ÷
የከፍተኛነትህም ፡ ሰይፍ ፡ ነው ።
ጠላቶችህም ፡ ይገዙልሃል ፤
አንተም ፡ ከፍታቸውን ፡ ትረግጣለህ ።

ምዕራፍ ፡ ፴፬ ።

፩ ሙሴም ፡ ከሞዓብ ፡ ሜዳ ፡ በኢያሪኮ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ ናባው ፡ ተራራ ፡ ወደ ፡ ፈስጋ ፡ ራስ ፡ ወጣ ፤ እግዚአብሔርም ፡ እስከ ፡ ዳን ፡ ድረስ ፡ ያለውን ፡ የገለዓድን ፡ ምድር ÷ ፪ የንፍታሌምንም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ÷ የኤፍሬምንና ፡ የምናሴንም ፡ ምድር ÷ እስከ ፡ ምዕራብም ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፡ ያለውን ፡ የይሁዳን ፡ ምድር ፡ ሁሉ ÷ ፫ ደቡቡንም ÷ እስከ ፡ ዞዓር ፡ ድረስ ፡ ያለውንም ፡ የዘንባባ ፡ ዛፎች ፡ ያሉባትን ፡ ከተማ ፡ የኢያሪኮን ፡ ሸለቆ ፡ ሜዳ ፡ አሳየው ። ፬ እግዚአብሔርም ፦ ለዘርህ ፡ እሰጣታለሁ ፡ ብዬ ፡ ለአብርሃምና ፡ ለይስሐቅ ፡ ለያዕቆብም ፡ የማልሁላቸው ፡ ምድር ፡ ይህች ፡ ናት ፤ በዓይንህ ፡ እንድ ታያት ፡ አደረግሁህ ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ወደዚያች ፡ አትሻገርም ፡ አለው ። ፭ የእግዚአብሔር ፡ ባሪያም ፡ ሙሴ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በዚያ ፡ በሞዓብ ፡ ምድር ፡ ሞተ ። ፮ በቤተ ፡ ፌጎርም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በሞዓብ ፡ ምድር ፡ በሸለቆው ፡ ውስጥ ፡ ተቀበረ ፤ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ መቃብሩን ፡ ማንም ፡ አላወቀም ። ፯ ሙሴም ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ ዕድሜው ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ዓመት ፡ ነበረ ፤ ዓይኑ ፡ አልፈዘዘም ÷ ጕልበቱም ፡ አልደነገዘም ። ፰ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በሞዓብ ፡ ሜዳ ፡ ሠላሳ ፡ ቀን ፡ ለሙሴ ፡ አለቀሱለት ፤ ለሙሴም ፡ ያለቀሱለት ፡ የልቅሶው ፡ ወራት ፡ ተፈጸመ ።

፱ ሙሴም ፡ እጆቹን ፡ ስለ ፡ ጫነበት ፡ የነዌ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡ የጥበብን ፡ መንፈስ ፡ ተሞላ ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ታዘዙለት ÷ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘው ፡ አደረጉ ። ፲ እግዚአብሔርን ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ እንዳወቀው ፡ እንደ ፡ ሙሴ ፡ ያለ ፡ ነቢይ ፡ ከዚያ ፡ ወዲህ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ አልተነሣም ፤ ፲፩ በግብፅ ፡ ምድር ፡ በፈርዖንና ፡ በባሪያዎቹ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በምድሪቱም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ምልክትንና ፡ ድንቅን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ላከው ፡ ያለ ÷ ፲፪ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ በጸናች ፡ እጅ ፡ ሁሉና ፡ በታላቅ ፡ ማስደንገጥ ፡ ሁሉ ፡ እንዳደረገው ፡ እንደ ፡ ሙሴ ፡ ያለ ፡ አልተነሣም ።

# መጽሐፈ ፡ ኢያሱ ፡ ወልደ ፡ ነዌ ።

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ የእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሙሴን ፡ አገልጋይ ፡ የነዌን ፡ ልጅ ፡ ኢያሱን ፡ እንዲህ ፡ ፪ ብሎ ፡ ተናገረው ፦ ባሪያዬ ፡ ሙሴ ፡ ሞቶአል ፤ አሁንም ፡ አንተና ፡ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ተነሥታችሁ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወደምሰጣቸው ፡ ፫ ምድር ፡ ይህን ፡ ዮርዳኖስን ፡ ተሻገሩ ። ለሙሴ ፡ እንደ ፡ ነገርሁት ፡ የእግራችሁ ፡ ጫማ ፡ የሚረግጠውን ፡ ቦታ ፡ ሁሉ ፡ ለእናንተ ፡ ሰጥቼአለሁ ። ፬ ከምድረ ፡ በዳው ፡ ከዚህም ፡ ከሊባኖስ ፡ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ወንዝ ፡ እስከ ፡ ኤፍራጥስ ፡ ድረስ ፡ የኬጢያውያን ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ፀሐይ ፡ መግቢያ ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፡ ዳርቻ ፭ ችሁ ፡ ይሆናል ። በሕይወትህ ፡ ዕድሜ ፡ ሁሉ ፡ ማንም ፡ አይቋቋምህም ፤ ከሙሴ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እንዲሁ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ እሆናለሁ ፤ ፮ አልጥልህም ÷ አልተውህም ። ለአባቶቻቸው ፦ እሰጣችኋለሁ ፡ ብዬ ፡ የማልሁላቸውን ፡ ምድር ፡ ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ታወርሳለህና ፡ ጽና ÷ አይዞህ ። ፯ ነገር ፡ ግን ፡ ጽና ÷ እጅግ ፡ በርታ ፤ ባሪያዬ ፡ ሙሴ ፡ ያዘዘህን ፡ ሕግ ፡ ሁሉ ፡ ጠብቅ ÷ አድርገውም ፤ በምትሄድበትም ፡ ሁሉ ፡ እንዲከናወንልህ ፡ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ አትበል ። ፰ የዚህ ፡ ሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ ከአፍህ ፡ አይለይ ÷ ነገር ፡ ግን ፡ የተጻፈበትን ፡ ሁሉ ፡ ትጠብቅና ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ በቀንም ፡ በሌሊትም ፡ አስበው ፤ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ መንገድህ ፡ ይቀናልሃል ፡ ይከናወንልሃልም ። ፱ በምትሄድበት ፡ ሁሉ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነውና ፡ ጽና ÷ አይዞህ ፤ አትፍራ ÷ አትደንግጥ ፡ ብዬ ፡ አላዘዝሁህምን ?

፲ ፡ ፲፩ ኢያሱም ፡ የሕዝቡን ፡ አለቆች ፦ በሰፈሩ ፡ መካከል ፡ እለፉ ÷ ሕዝቡንም ፦ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ ወደሚሰጣ

ችሁ ፡ ምድር ፡ እስከ ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ይህን ፡ የዮር
ዳኖስን ፡ ተሻግራችሁ ፡ ልትወርሱአት ፡ ትገቡ
ባታላችሁና ፡ ስንቃችሁን ፡ አዘጋጁ ፡ ብላችሁ ፡
እዘዙአቸው ፡ ብሎ ፡ አዘዘ ።

፲፪ ኢያሱም ፡ የሮቤልን ፡ ልጆች ፡ የጋድንም ፡
ልጆች ፡ የምናሴንም ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ እንዲህ ፡
፲፫ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— የእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡
ሙሴ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ያዘዛችሁን ፡ ቃል ፡ አስቡ ፡—
አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያሳርፋችኋል ÷
፲፬ ይህችንም ፡ ምድር ፡ ይሰጣችኋል ። ሚስቶቻች
ሁና ፡ ልጆቻችሁ ፡ ከብቶቻችሁም ፡ ሙሴ ፡ በዮ
ርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በሰጣችሁ ፡ ምድር ፡ ይቀመጡ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ እናንተ ÷ ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡ ሁሉ ÷
ተሰልፋችሁ ፡ በወንድሞቻችሁ ፡ ፊት ፡ ተሻገሩ ÷
፲፭ እርዱአቸውም ÷ እግዚአብሔር ፡ እናንተን ፡
እንዳሳረፋችሁ ፡ ወንድሞቻችሁን ፡ እስኪያሳ
ርፍ ፡ ድረስ ÷ እነርሱም ፡ ደግሞ ፡ አምላካችሁ ፡
እግዚአብሔር ፡ የሚሰጣቸውን ፡ ምድር ፡ እስኪ
ወርሱ ፡ ድረስ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ በፀሐይ ፡ መውጫ ፡ ወደ ፡
ሰጣችሁ ፡ ወደ ፡ ርስታችሁ ፡ ምድር ፡ ትመለሳ
፲፮ ላችሁ ፡ ትወርሱአትማላችሁ ። እነርሱም ፡ ለኢ
ያሱ ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ መለሱለት ፡— ያዘዝኸ
ንን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እናደርጋለን ፡ ወደምትልክ
፲፯ ንም ፡ ስፍራ ፡ እንሄዳለን ። በሁሉም ፡ ለሙሴ ፡
እንደ ፡ ታዘዝን ፡ እንዲሁ ፡ ለአንተ ፡ ደግሞ ፡
እንታዘዛለን ፤ ብቻ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡
ከሙሴ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡
፲፰ ይሁን ። በትእዛዝህ ፡ የሚያምፅ ፡ ሁሉ ፡ የም
ታዝዘውንም ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ የማይሰማ ÷ እርሱ ፡
ይገደል ፤ ብቻ ፡ ጽና ÷ አይዞህ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ የነዌም ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡— ሄዳችሁ ፡ ምድ
ሪቱንና ፡ ኢያሪኮን ፡ እዩ ፡ ብሎ ፡ ከሰጢም ፡
ሁለት ፡ ሰላዮች ፡ በስውር ፡ ላከ ። ሄዱም ፤
ረዓብም ፡ ወደሚሉአት ፡ ጋለሞታ ፡ ቤት ፡ ገቡ ÷
፪ በዚያም ፡ አደሩ ። የኢያሪኮም ፡ ንጉሥ ፡—
እነሆ ÷ ሰዎች ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ አገሩን ፡
ሊሰልሉ ፡ ወደዚህ ፡ በሌሊት ፡ ገቡ ፡ ሲባል ፡
፫ ወሬ ፡ ሰማ ። የኢያሪኮም ፡ ንጉሥ ፡— አገሩን ፡
ሁሉ ፡ ሊሰልሉ ፡ መጥተዋልና ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡
የመጡትን ፡ ወደ ፡ ቤትሽም ፡ የገቡትን ፡ ሰዎች ፡
፬ አውጪ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ረዓብ ፡ ላከ ። ሴቲቱም ፡
ሁለቱን ፡ ሰዎች ፡ ወስዳ ፡ሸሸገቻቸው ፤ እርስ
ዋም ፡— አዎን ÷ ሰዎቹ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጡ ÷
ከወዴት ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ግን ፡ አላወቅሁም ፤
፭ በሩም ፡ ሲዘጋ ፡ ሲጨልምም ፡ ሰዎቹ ፡ ወጡ ፤
ወዴት ፡ እንደ ፡ ሄዱ ፡ አላውቅም ፤ ፈጥናችሁ ፡
አሳድዱአቸው ÷ ታገኙአቸውማላችሁ ፡ አለች ።
፮ እርስዋ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ሰገነቱ ፡ አውጥታቸው ፡
ነበር ፤ በዚያም ፡ በረበረበችው ፡ በተልባ ፡
፯ እግር ፡ ውስጥ ፡ ሸሽጋቸው ፡ ነበር ። ሰዎቹም ፡
ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡ መሻገሪያ ፡ በሚወስደው ፡ መን
ገድ ፡ አሳደዱአቸው ፤ አሳዳጆችም ፡ ከወጡ ፡
በኋላ ፡ በሩ ፡ ተቈለፈ ።

፰ እነዚህም ፡ ሳይተኙ ፡ ሴቲቱ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡
፱ ወደ ፡ ሰገነቱ ፡ ወጣች ። ሰዎቹንም ፡ እንዲህ ፡ አለ
ቻቸው ፡— እግዚአብሔር ፡ ምድሪቱን ፡ እንደ ፡
ሰጣችሁ ÷ እናንተንም ፡ መፍራት ፡ በላያችን ፡
እንደ ፡ ወደቀ ÷ በምድሪቱም ፡ የሚኖሩት ፡ ሁሉ ፡
፲ ከፊታችሁ ፡ እንደ ፡ ቀለጡ ፡ አወቅሁ ። ከግ
ብፅ ፡ ምድር ፡ በወጣችሁ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡
የኤርትራን ፡ ባሕር ፡ በፊታችሁ ፡ እንዳደረቀ ÷
በዮርዳኖስም ፡ ማዶ ፡ በነበሩት ፡ እናንተም ፡
ፈጽማችሁ ፡ ባጠፋችኋቸው ፡ በሁለቱ ፡ በአሞ
ራውያን ፡ ነገሥታት ÷ በሴዎንና ፡ በዐግ ፡ ያደ
፲፩ ረጋችሁትን ፡ ሰምተናል ። ይህንም ፡ ነገር ፡ ሰም
ተን ፡ ልባችን ፡ ቀለጠ ፤ አምላካችሁም ፡ እግዚ
አብሔር ፡ በላይ ፡ በሰማይ ፡ በታችም ፡ በምድር ፡
እርሱ ፡ አምላክ ፡ ነውና ፡ ከእናንተ ፡ የተነሣ ፡
ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ለማንም ፡ ነፍስ ፡ አልቀረለትም ።
፲፪ አሁንም ÷ እባካችሁ ÷ በእግዚአብሔር ፡ ማሉ
ልኝ ÷ በእውነትም ፡ ምልክት ፡ ስጡኝ ÷ እኔ ፡
ለእናንተ ፡ ቸርነት ፡ እንደ ፡ ሠራሁ ፡ እናንተ ፡
ደግሞ ፡ ለአባቴ ፡ ቤት ፡ ቸርነት ፡ እንድትሠሩ ÷
፲፫ አባቴንና ፡ እናቴንም ፡ ወንድሞቼንና ፡ እኅቶቼ
ንም ፡ ያላቸውንም ፡ ሁሉ ፡ እንድታድኑ ÷ ሰው
፲፬ ነታችንንም ፡ ከሞት ፡ እንድታድኑ ። ሰዎቹም ፡—
ይህን ፡ ነገራችንን ፡ ባትገልጪ ፡ ነፍሳችን ፡ በነ
ፍሳችሁ ፡ ፋንታ ፡ ለሞት ፡ ይሆናል ፤ እግዚአ
ብሔርም ፡ ምድሪቱን ፡ በሰጠን ፡ ጊዜ ፡ ከአንቺ ፡
ጋር ፡ ቸርነትንና ፡ እውነትን ፡ እናደርጋለን ፡
አሉአት ።

፲፭ ቤትዋም ፡ በከተማ ፡ ቅጥር ፡ የተጠጋ ፡ ነበ
ረና ÷ እርስዋም ፡ በቅጥሩ ፡ ላይ ፡ ተቀምጣ ፡ ነበ
ርና ፡ ከመስኮቱ ፡ በገመድ ፡ አወረደቻቸው ።
፲፮ እርስዋም ፡— አሳዳጆቹ ፡ እንዳያገኙአችሁ ፡
ወደ ፡ ተራራው ፡ ሂዱ ፤ አሳዳጆቹም ፡ እስኪ
መለሱ ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ተሰውራ
ችሁ ፡ ተቀመጡ ፤ ኋላም ፡ መንገዳችሁን ፡ ትሄ
፲፯ ዳላችሁ ፡ አለቻቸው ። ሰዎቹም ፡ አሉአት ፡—
እኛ ፡ ከዚህ ፡ ካማልሽን ፡ መሐላ ፡ ንጹሐን ፡ እን
፲፰ ሆናለን ። እነሆ ÷ እኛ ፡ ወደ ፡ አገሩ ፡ በገባን ፡
ጊዜ ፡ ይህን ፡ ቀይ ፡ ፈትል ፡ እኛን ፡ በወረድሽ
በት ፡ መስኮት ፡ በኩል ፡ እሰሪው ፤ አባትሽንም ፡
እናትሽንም ፡ ወንድሞችሽንም ፡ የአባትሽንም ፡
ቤተ ፡ ሰብ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡ ወደ ፡ ቤትሽ ፡
፲፱ ሰብስቢ ። ከቤትሽም ፡ ደጅ ፡ ወደ ፡ሜዳ ፡ የሚ
ወጣ ፡ ደሙ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ÷ እኛም ፡
ንጹሐን ፡ እንሆናለን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከአንቺ ፡
ጋር ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ያለውን ፡ አንድ ፡ እጅ ፡
ቢነካው ፡ ደሙ ፡ በእኛ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ።
፳ ይህንን ፡ ነገራችንን ፡ ግን ፡ ብትገልጪ ፡ ከዚህ ፡
ካማልሽን ፡ መሐላ ፡ ንጹሐን ፡ እንሆናለን ።
፳፩ እርስዋም ፡— እንደ ፡ ቃላችሁ ፡ ይሁን ፡ አለች ፤
ሰደደቻቸውም ፡ እነርሱም ፡ ሄዱ ፤ ቀዩንም ፡
ፈትል ፡ በመስኮቱ ፡ በኩል ፡ አንጠለጠለችው ።

፳፪ እነርሱም ፡ ሄደው ፡ ወደ ፡ ተራራው ፡ ደረሱ ፥ አሳዳጆቹም ፡ እስኪመለሱ ፡ ድረስ ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ በዚያ ፡ ተቀመጡ ፤ አሳዳጆቹም ፡ በመንገዱ ፡ ሁሉ ፡ ፈልገው ፡ አላገኙአቸውም ። ፳፫ ሁለቱም ፡ ሰዎች ፡ ተመለሱ ፥ ከተራራውም ፡ ወርደው ፡ ተሻገሩ ፥ ወደ ፡ ነዌም ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢያሱ ፡ መጡ ፤ የደረሰባቸውንም ፡ ሁሉ ፡ አወሩለት ። ፳፬ ኢያሱንም ፦ በእውነት ፡ እግዚአብሔር ፡ አገሩን ፡ ሁሉ ፡ በእጃችን ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶአል ፤ በአገሩም ፡ ውስጥ ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በፊታችን ፡ ይቀልጣሉ ፡ አሉት ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ኢያሱም ፡ ማልዶ ፡ ተነሣ ፥ እርሱና ፡ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ከሰጢም ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡ መጡ ፤ ሳይሻገሩም ፡ በዚያ ፡ አደሩ ። ፪ ከሦስት ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ አለቆች ፡ በሰፈሩ ፡ መከከል ፡ አለፉ ። ፫ ሕዝቡን ፦ የአምላካችሁን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦትና ፡ ሌዋውያን ፡ ካህናት ፡ ተሸክመውት ፡ ባያችሁ ፡ ጊዜ ፥ ከሰፈራችሁ ፡ ተነሥታችሁ ፡ ተከተሉት ። ፬ በእናንተና ፡ በታቦቱ ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ርቀት ፡ በስፍር ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ክንድ ፡ ያህል ፡ ይሁን ፤ በዚህ ፡ መንገድ ፡ በፊት ፡ አልሄዳችሁበትምና ፡ የምትሄዱበትን ፡ መንገድ ፡ እንድታውቁ ፡ ወደ ፡ ታቦቱ ፡ አትቅረቡ ፡ ብለው ፡ አዘዙ ።

፭ ኢያሱም ፡ ሕዝቡን ፦ ነገ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመካከላችሁ ፡ ድንቅ ፡ ነገር ፡ ያደርጋልና ፡ ተቀደሱ ፡ አለ ። ፮ ኢያሱም ፡ ካህናቱን ፦ የቃል ፡ ኪዳኑን ፡ ታቦት ፡ ተሸከማችሁ ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ እለፉ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፤ የቃል ፡ ኪዳኑንም ፡ ታቦት ፡ ተሸክመው ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ አለፉ ።

፯ እግዚአብሔርም ፡ ኢያሱን ፦ ከሙሴ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እንዲሁ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ መሆኔን ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ በዚህ ፡ ቀን ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ዓይን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርግህ ፡ ዘንድ ፡ እጀምራለሁ ። ፰ አንተም ፡ የቃል ፡ ኪዳኑን ፡ ታቦት ፡ የሚሸከሙትን ፡ ካህናት ፦ በዮርዳኖስ ፡ ውኃ ፡ ዳር ፡ ስትደርሱ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ውስጥ ፡ ቁሙ ፡ ብለህ ፡ እዘዝ ፡ አለው ።

፱ ኢያሱም ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፦ ወደዚህ ፡ ቀርባችሁ ፡ የአምላካችሁን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስሙ ፡ አለ ። ፲ ኢያሱም ፡ አለ ፦ ሕያው ፡ አምላክ ፡ በመካከላችሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ እርሱም ፡ ከፊታችሁ ፡ ከነዓናዊውን ፡ ኬጢያዊውንም ፡ ኤዊያዊውንም ፡ ፌርዛዊውንም ፡ ጌርጌሳዊውንም ፡ አሞራዊውንም ፡ ኢያቡሳዊውንም ፡ ፈጽሞ ፡ እንዲያወጣ ፡ በዚህ ፡ ታውቃላችሁ ። ፲፩ እነሆ ፥ የምድር ፡ ሁሉ ፡ ጌታ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ በፊታችሁ ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ያልፋል ። ፲፪ አሁንም ፡ ከእስራኤል ፡ ነገዶች ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ምረጡ ፤ ከየነገዱ ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ይሁን ። ፲፫ እንዲህም ፡ ይሆናል ፤ የምድርን ፡ ሁሉ ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ የተሸከሙ ፡ ካህናት ፡ እግር ፡ ጫማ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ውኃ ፡ ውስጥ ፡ ሲቆም ፥ ከላይ ፡ የሚወርደው ፡ የዮርዳኖስ ፡ ውኃ ፡ ይቋረጣል ፤ እንደ ፡ ክምርም ፡ ሆኖ ፡ ይቆማል ።

፲፬ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ሕዝቡ ፡ ዮርዳኖስን ፡ ሊሻገሩ ፡ ከየድንኳናቸው ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፥ የቃል ፡ ኪዳኑን ፡ ታቦት ፡ የተሸከሙ ፡ ካህናት ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ ይሄዱ ፡ ነበር ። ፲፭ እንደ ፡ መከር ፡ ወራት ፡ ሁሉ ፡ ዮርዳኖስ ፡ እጅግ ፡ ሞልቶ ፡ ነበርና ፡ ታቦት ፡ ተሸካሚዎቹ ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ሲደርሱ ፥ ታቦቱንም ፡ የተሸከሙት ፡ የካህናቱ ፡ እግሮች ፡ በውኃው ፡ ዳር ፡ ሲጠልቁ ፥ ፲፮ ከላይ ፡ የሚወርደው ፡ ውኃ ፡ ቆመ ፤ በጻርታን ፡ አጠገብ ፡ ባለችው ፡ አዳም ፡ በምትባል ፡ ከተማ ፡ በሩቅ ፡ ቆሞ ፡ በአንድ ፡ ክምር ፡ ተነሣ ፤ ወደ ፡ ዓረብ ፡ ባሕር ፡ ወደ ፡ ጨው ፡ ባሕር ፡ የሚወርደው ፡ ውኃ ፡ ፈጽሞ ፡ ተቋረጠ ፤ ሕዝቡም ፡ በኢያሪኮ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ተሻገሩ ። ፲፯ የእግዚአብሔርም ፡ የቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ የተሸከሙ ፡ ካህናት ፡ በዮርዳኖስ ፡ መካከል ፡ በደረቅ ፡ መሬት ፡ ጸንተው ፡ ቆመው ፡ ነበር ፥ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ዮርዳኖስን ፡ ፈጽመው ፡ እስኪሻገሩ ፡ ድረስ ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ በደረቅ ፡ መሬት ፡ ተሻገሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ዮርዳኖስን ፡ ፈጽመው ፡ በተሻገሩ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ፪ ኢያሱን ፦ ከሕዝቡ ፡ ከየነገዱ ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ ሰው ፥ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ምረጥና ፦ ፫ በዮርዳኖስ ፡ መካከል ፡ የካህናት ፡ እግር ፡ ከቆመበት ፡ ስፍራ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ድንጋዮች ፡ አንሡ ፤ ተሸከማችሁም ፡ በዚህ ፡ ሌሊት ፡ በምታድሩበት ፡ ስፍራ ፡ አኑሩአቸው ፡ ብለህ ፡ እዘዛቸው ፡ አለው ።

፬ ኢያሱም ፡ ከየነገዱ ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ ሰው ፥ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ያዘጋጃቸውን ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ጠራ ። ፭ ኢያሱም ፡ አላቸው ፦ በአምላካችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡ መካከል ፡ እለፉ ፤ ከእናንተም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ቍጥር ፡ በጫንቃው ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ ድንጋይ ፡ ከዚያ ፡ ይሸከም ። ፮ ይህም ፡ በመካከላችሁ ፡ ምልክት ፡ ይሆናል ፤ ልጆቻችሁም ፡ በሚመጣው ፡ ዘመን ፦ የእነዚህ ፡ ድንጋዮች ፡ ነገር ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብለው ፡ ሲጠይቁአችሁ ፥ ፯ እናንተ ፦ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ የዮርዳኖስ ፡ ውኃ ፡ ስለ ፡ ተቋረጠ ፡ ነው ፤ ዮርዳኖስን ፡ በተሻገረ ፡ ጊዜ ፡ የዮርዳኖስ ፡ ውኃ ፡ ተቋረጠ ፥ እነዚህም ፡ ድንጋዮች ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ለዘላለም ፡ መታሰቢያ ፡ ይሆናሉ ፡ ትሉአቸዋላችሁ ።

፰ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ኢያሱ ፡ እንዳዘዘ ፡ አደረጉ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ኢያሱን ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ በእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ቍጥር ፡ ከዮር

ዳኖስ ፡ መካከል ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ድንጋዮች ፡
አንሥተው ፡ ወደሚያድሩበት ፡ ስፍራ ፡ ወሰዱ ÷
፱ በዚያም ፡ አኖሩአቸው ። ኢያሱም ፡ የቃል ፡
ኪዳኑን ፡ ታቦት ፡ የተሸከሙ ፡ ካህናት ፡ እግ
ሮች ፡ በቆሙበት ፡ ስፍራ ፡ በዮርዳኖስ ፡ መካ
ከል ፡ ሌሎችን ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ድንጋዮች ፡
ተከለ ፤ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ አሉ ።
፲ ሙሴም ፡ ኢያሱን ፡ እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ÷ እግዚ
አብሔር ፡ ኢያሱን ፡ ለሕዝቡ ፡ እንዲነግር ፡ ያዘ
ዘው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ ታቦ
ቱን ፡ የተሸከሙ ፡ ካህናት ፡ በዮርዳኖስ ፡ መካ
ከል ፡ ቆመው ፡ ነበርና ፤ ሕዝቡም ፡ ፈጥነው ፡
፲፩ ተሻገሩ ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ፈጽመው ፡ በተሻ
ገሩ ፡ ጊዜ ÷ ሕዝቡ ፡ እያዩ ፡ የእግዚአብሔር ፡
፲፪ ታቦትና ፡ ካህናቱ ፡ ተሻገሩ ። ሙሴም ፡ እንዳ
ዘዛቸው ፡ የሮቤል ፡ ልጆች ÷ የጋድም ፡ ልጆች ÷
የምናሴም ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ተሰልፈው ፡ በእ
፲፫ ስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ተሻገሩ ። አርባ ፡
ሺህ ፡ ያህል ፡ ሰዎች ፡ ጋሻና ፡ ጦራቸውን ፡
ይዘው ፡ ለሰልፍ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ወደ ፡
፲፬ ኢያሪኮ ፡ ሜዳ ፡ ተሻገሩ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ኢያሱን ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡
ከፍ ፡ አደረገው ፤ ሙሴንም ፡ እንደ ፡ ፈሩ ፡ በዕ
ድሜው ፡ ሁሉ ፡ ፈሩት ።

፲፭፡፲፮ እግዚአብሔርም ፡ ኢያሱን ፡— የምስክሩን ፡
ታቦት ፡ የሚሸከሙትን ፡ ካህናት ፡ ከዮርዳኖስ ፡
፲፯ እንዲወጡ ፡ እዘዝ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ። ኢያ
ሱም ፡ ካህናትን ፡— ከዮርዳኖስ ፡ ውጡ ፡ ብሎ ፡
፲፰ አዘዛቸው ። የእግዚአብሔርንም ፡ የቃል ፡ ኪዳ
ኑን ፡ ታቦት ፡ የተሸከሙ ፡ ካህናት ፡ ከዮርዳኖስ ፡
መካከል ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ÷ የካህናቱም ፡ እግር ፡
ጫማ ፡ ደረቅ ፡ መሬት ፡ መርገጥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ÷
የዮርዳኖስ ፡ ውኃ ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ተመለሰ ÷
ቀድሞም ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ በዳሩ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡
ሄደ ።

፲፱ ሕዝቡም ፡ በመጀመሪያው ፡ ወር ፡ በአሥረ
ኛው ፡ ቀን ፡ ከዮርዳኖስ ፡ ወጡ ÷ በኢያሪኮም ፡
ዳርቻ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ በጌልገላ ፡ ሰፈሩ ።
፳ ከዮርዳኖስም ፡ ውስጥ ፡ የወሰዱአቸውን ፡ እነዚ
ያን ፡ አሥራ ፡ ሁለቱን ፡ ድንጋዮች ፡ ኢያሱ ፡
፳፩ በጌልገላ ፡ አቆማቸው ። ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— በሚመጣው ፡
ዘመን ፡ ልጆቻችሁ ፡ አባቶቻቸውን ፡— እነዚህ ፡
ድንጋዮች ፡ ምንድር ፡ ናቸው ? ብለው ፡ ሲጠ
፳፪ ይቁ ÷ ለልጆቻችሁ ፡ እንዲህ ፡ ብላችሁ ፡ ታስታ
ውቃላችሁ ፡— እስራኤል ፡ ይህን ፡ ዮርዳኖስን ፡
፳፫ በደረቅ ፡ ተሻገረ ፤ እስክንሻገር ፡ ድረስ ፡ አምላ
ካችሁ ፡ የኤርትራን ፡ ባሕር ፡ ከፊታችን ፡ እንዳ
ደረቀ ፡ እንዲሁ ፡ እስክትሻገሩ ፡ ድረስ ፡ አምላ
ካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ የዮርዳኖስን ፡ ውኃ ፡
፳፬ ከፊታችሁ ፡ አደረቀ ። ይኸውም ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ እጅ ፡ ጠንካራ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ የምድር ፡
አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ እንዲያውቁ ÷ አምላካችሁንም ፡
እግዚአብሔርን ፡ ለዘላለሙ ፡ እንድትፈሩ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በምዕ
ራብ ፡ በኩል ፡ የነበሩት ፡ የአሞራውያን ፡ ነገሥ
ታት ፡ ሁሉ ÷ በባሕሩም ፡ አጠገብ ፡ የነበሩ ፡ የከ
ነዓናውያን ፡ ነገሥት ፡ ሁሉ ÷ እግዚአብሔር ፡
ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ የዮርዳኖስን ፡ ውኃ ፡
እስኪሻገሩት ፡ ድረስ ፡ እንዳደረቀ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ÷
ልባቸው ፡ ቀለጠ ፡ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ የተ
ነሣ ፡ ነፍስ ፡ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ አልቀረላቸውም ።

፪ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ እግዚአብሔር ፡ ኢያሱን ፡—
የባልጩት ፡ መቍረጫ ፡ ሥርተህ ፡ የእስራኤልን ፡
ልጆች ፡ ሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡ ግረዛቸው ፡ አለው ።
፫ ኢያሱም ፡ የባልጩት ፡ መቍረጫ ፡ ሠርቶ ፡ የግ
ርዛት ፡ ኮረብታ ፡ በተባለ ፡ ስፍራ ፡ የእስራኤልን ፡
፬ ልጆች ፡ ገረዘ ። ኢያሱ ፡ የገረዘበትም ፡ ምክን
ያት ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ከግብፅ ፡ የወጡት ፡ ሕዝብ ፡
ወንዶች ፡ ሰልፈኞች ፡ ሁሉ ፡ ከግብፅ ፡ ከወጡ ፡
በኋላ ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ሞቱ ።
፭ የወጡት ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ተገርዘው ፡ ነበር ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ከግብፅ ፡ በወጡበት ፡ መንገድ ፡ በም
ድረ ፡ በዳ ፡ የተወለዱት ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ አልተ
፮ ገረዙም ፡ ነበር ። እግዚአብሔርም ፡ ወተትና ፡
ማር ፡ የምታፈስሰውን ፡ ምድር ፡ ለእኛ ፡ ይሰጠን ፡
ዘንድ ፡ ለአባቶቻቸው ፡ የማለላቸውን ፡ ምድር ፡
እንዳያሳያቸው ፡ የማለላቸው ÷ ከግብፅ ፡ የወጡ ፡
የእግዚአብሔርንም ፡ ቃል ፡ ያልሰሙ ÷ እነዚያ ፡
ሰልፈኞች ፡ ሁሉ ፡ እስኪጠፉ ፡ ድረስ ፡ የእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡
፯ ይሄዱ ፡ ነበር ። ልጆቻቸውን ፡ በእነርሱ ፡ ፋንታ ፡
አስነሣ ÷ እነዚህንም ፡ ኢያሱ ፡ ገረዛቸው ፤ በመ
ንገድ ፡ ሳሉ ፡ ስላልገረዙአቸው ፡ ሸለፈታሞች ፡
፰ ነበሩና ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ፈጽመው ፡ በተገ
ረዙ ፡ ጊዜ ፡ እስኪድኑ ፡ ድረስ ፡ በሰፈር ፡ ውስጥ ፡
፱ በየስፍራቸው ፡ ተቀመጡ ። እግዚአብሔርም ፡
ኢያሱን ፡— ዛሬ ፡ የግብፅን ፡ ነውር ፡ ከእናንተ ፡
ላይ ፡ አንከባልያለሁ ፡ አለው ፤ ስለዚህ ፡ የዚያ ፡
ስፍራ ፡ ስም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ጌልገላ ፡ ተብሎ ፡
ተጠራ ።

፲ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በጌልገላ ፡ ሰፈሩ ፤
ከወሩም ፡ በአሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ በመሸ ፡
፲፩ ጊዜ ፡ በኢያሪኮ ፡ ሜዳ ፡ ፋሲካ ፡ አደረጉ ። ከፋ
ሲካውም ፡ በኋላ ፡ በነጋው ፡ የምድሪቱን ፡ ፍሬ ፡
የቂጣ ፡ እንጎቻ ፡ ቆሎም ፡ በዚያው ፡ ቀን ፡ በሉ ።
፲፪ በነጋውም ፡ ከምድሪቱ ፡ ፍሬ ፡ ከበሉ ፡ በኋላ ፡
መናው ፡ ቀረ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ለእስራኤል ፡
ልጆች ፡ መና ፡ አልመጣላቸውም ፤ ነገር ፡ ግን ፡
በዚያው ፡ ዓመት ፡ የከነዓንን ፡ ምድር ፡ ፍሬ ፡
በሉ ።

፲፫ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ኢያሱ ፡ በኢያሪኮ ፡ አጠ
ገብ ፡ ሳለ ፡ ዓይኑን ፡ አንሥቶ ፡ ተመለከተ ÷ እነ
ሆም ÷ የተመዘዘ ፡ ሰይፍ ፡ በእጁ ፡ የያዘ ፡ ሰው ፡
በፊቱ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፤ ኢያሱም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡
ቀርቦ ፡— ከእኛ ፡ ወገን ፡ ወይስ ፡ ከጠላቶቻችን ፡

፲፬ ወገን ፡ ነህን? አለው ። እርሱም ፡— አይደለሁም ፤ እኔ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሠራዊት ፡ አለቃ ፡ ሆኜ ፡ አሁን ፡ መጥቼአለሁ ፡ አለ ። ኢያሱም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ በግምባሩ ፡ ተደፍቶ ፡ ሰገደና ፡— ጌታዬ ፡ ለባሪያው ፡ የሚነግረው ፡ ምንድር ፡ ነው ? ፲፭ አለው ። የእግዚአብሔርም ፡ ሠራዊት ፡ አለቃ ፡ ኢያሱን ፡— አንተ ፡ የቆምህበት ፡ ስፍራ ፡ የተቀደሰ ፡ ነውና ፡ ጫማህን ፡ ከእግርህ ፡ አውልቅ ፡ አለው ። ኢያሱም ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ኢያሪኮም ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የተነሣ ፡ ፈጽማ ፡ ተዘግታ ፡ ነበር ፤ ወደ ፡ እርስዋ ፡ የሚገባ ፡ ከእርስዋም ፡ የሚወጣ ፡ ማንም ፡ አልነበ ፪ ረም ። እግዚአብሔርም ፡ ኢያሱን ፡ አለው ፡— ተመልከት ÷ ኢያሪኮንና ፡ ንጉሥዋን ፡ ጽኑዓን ፡ ፫ ኃያላንዋንም ፡ በእጅህ ፡ ሰጥቼአለሁ ። ሰልፈኞቻችሁ ፡ ሁሉ ፡ ከተማይቱን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ይዞሩአት ፤ እንዲሁም ፡ ስድስት ፡ ቀን ፡ አድርጉ ። ፬ ሰባትም ፡ ካህናት ፡ ሰባት ፡ ቀንደ ፡ መለከት ፡ በታቦቱ ፡ ፊት ፡ ይሸከሙ ፤ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ ከተማይቱን ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ዙሩ ÷ ካህናቱም ፡ ፭ ቀንደ ፡ መለከቱን ፡ ይንፉ ። ቀንደ ፡ መለከቱም ፡ በለማቋረጥ ፡ ሲነፋ ÷ የመለከቱንም ፡ ድምፅ ፡ ስትሰሙ ÷ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ታላቅ ፡ ጩኸት ፡ ይጩኹ ፤ የከተማይቱም ፡ ቅጥር ፡ ይወድቃል ÷ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ አቅንቶ ፡ ይገባበ ፮ ታል ። የነዌም ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡ ካህናቱን ፡ ጠርቶ ፡— የቃል ፡ ኪዳኑን ፡ ታቦት ፡ ተሸከሙ ÷ ሰባትም ፡ ካህናት ፡ ሰባት ፡ ቀንደ ፡ መለከት ፡ ወስደው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ ይሂዱ ፡ ፯ አላቸው ። ሕዝቡንም ፡— ሂዱ ÷ ከተማይቱንም ፡ ዙሩ ÷ ሰልፈኞችም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ ይሂዱ ፡ አለ ።

፰ ኢያሱም ፡ ለሕዝቡ ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ÷ ሰባቱ ፡ ካህናት ፡ ሰባቱን ፡ ቀንደ ፡ መለከት ፡ ይዘው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሄዱ ፡ ቀንደ ፡ መለከቱንም ፡ ነፉ ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ ፱ ይከተላቸው ፡ ነበር ። ሰልፈኞቹም ፡ ቀንደ ፡ መለከቱን ፡ በሚነፉ ፡ በካህናቱ ፡ ፊት ፡ ይሄዱ ፡ ነበር ÷ የቀረውም ፡ ሕዝብ ፡ ከታቦቱ ፡ በኋላ ፡ ይሄድ ፡ ነበር ÷ ካህናቱም ፡ እየሄዱ ፡ ቀንደ ፡ መለ ፲ ከቱን ፡ ይነፉ ፡ ነበር ። ኢያሱም ፡ ሕዝቡን ፡— እኔ ፡— ጩኹ ፡ እስከምልበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ አትጩኹ ÷ ድምፃችሁንም ፡ አታንሡ ÷ ከአፋችሁም ፡ አንድ ፡ ቃል ፡ አይውጣ ፤ በዚያን ፡ ፲፩ ጊዜ ፡ ትጮኻላችሁ ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ። እንዲሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ከተማይቱን ፡ አዞረው ፤ እነርሱም ፡ ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ ተመልሰው ፡ አደሩ ።

፲፪ ኢያሱም ፡ ማለዳ ፡ ተነሣ ፡ ካህናቱም ፡ የእግ ፲፫ ዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ተሸከሙ ። ሰባቱም ፡ ካህናት ፡ ሰባት ፡ ቀንደ ፡ መለከት ፡ ይዘው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ ይሄዱ ፡ ነበር ፡ ቀንደ ፡ መለከቱንም ፡ ይነፉ ፡ ነበር ፤ ሰልፈኞቹም ፡ በፊታቸው ፡ ይሄዱ ፡ ነበር ፤ የቀሩትም ፡ ሕዝብ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ በኋላ ፡ ይመጡ ፡ ነበር ÷ ካህናቱም ፡ እየሄዱ ፡ ቀንደ ፡ መለከቱን ፡ ይነፉ ፡ ነበር ። ፲፬ በሁለተኛውም ፡ ቀን ፡ ከተማይቱን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ዞረው ፡ ወደ ፡ ሰፈር ፡ ተመለሱ ፤ ስድስት ፡ ቀንም ፡ እንዲህ ፡ አደረጉ ።

፲፭ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ በነጋ ፡ ጊዜ ፡ ማልደው ፡ ተነሡ ÷ እንደዚህም ፡ ሥርዓት ፡ ከተማይቱን ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ዞሩ ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ ብቻ ፡ ከተማ ይቱን ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ዞሩ ። ፲፮ በሰባተኛውም ፡ ጊዜ ፡ ካህናቱ ፡ ቀንደ ፡ መለከቱን ፡ ሲነፉ ፡ ኢያሱ ፡ ሕዝቡን ፡ አለ ፡— እግዚአብሔር ፡ ከተማይቱን ፡ ሰጥቶአችኋልና ፡ ጩኹ ። ፲፯ ከተማይቱም ፡ በእርስዋም ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እርም ፡ ይሆናሉ ፤ የላክናቸውን ፡ መልክተኞች ፡ ስለ ፡ ሸሸገች ፡ ጋለሞታይቱ ፡ ረዓብ ፡ ከእርስዋም ፡ ጋር ፡ በቤትዋ ፡ ውስጥ ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ ብቻ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉ ። ፲፰ እናንተ ፡ ግን ፡ እርም ፡ ከደረጋችሁት ፡ በኋላ ፡ እርም ፡ ከሆነው ፡ ነገር ፡ ራሳችሁን ፡ ጠብቁ ፤ እርም ፡ ከሆነው ፡ አንዳች ፡ የወሰዳችሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የእስራኤልን ፡ ሰፈር ፡ የተረገመ ፡ ታደርጉታላችሁ ÷ ታስጨንቁትማላችሁ ። ፲፱ ነገር ፡ ግን ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ ሁሉ ፡ የናስና ፡ የብረትም ፡ ዕቃ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ ፡ ይሁን ፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ግምጃ ፡ ቤት ፡ ይግባ ። ፳ ሕዝቡም ፡ ጮኹ ÷ ካህናቱም ፡ ቀንደ ፡ መለከቱን ፡ ነፉ ፤ ሕዝቡም ፡ የቀንደ ፡ መለከቱን ፡ ድምፅ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ታላቅ ፡ ጩኸት ፡ ጮኹ ÷ ቅጥሩም ፡ ወደቀ ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ አቅንቶ ፡ ወደ ፡ ፊቱ ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ ወጣ ÷ ከተማይቱንም ፡ ወሰዱ ። ፳፩ በከተማይቱም ፡ የነበሩትን ፡ ሁሉ ÷ ወንዱንና ፡ ሴቱን ÷ ሕፃኑንና ፡ ሽማግሌውን ÷ በሬውንም ፡ በጉንም ፡ አህያውንም ÷ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ ፈጽመው ፡ አጠፉ ።

፳፪ ኢያሱም ፡ ምድሪቱን ፡ የሰለሉ ፡ ሁለቱን ፡ ሰዎች ፡— ወደ ፡ ጋለሞታይቱ ፡ ቤት ፡ ግቡ ÷ ከዚያም ፡ ሴቲቱንና ፡ ያላትን ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ማላችሁላት ፡ አውጡ ፡ አላቸው ። ፳፫ ሰላዮቹም ፡ ብላቴናዎች ፡ ገብተው ፡ ረዓብን ÷ አባትዋንና ፡ እናትዋን ÷ ወንድሞችዋንም ÷ ያላትንም ፡ ሁሉ ÷ ቤተ ፡ ዘመዶችዋንም ፡ ሁሉ ፡ አወጡ ፤ ከእስራኤልም ፡ ሰፈር ፡ በውጭ ፡ አስቀመጡአቸው ።

፳፬ ከተማይቱንም ፡ በእርስዋም ፡ የነበረውን ፡ ሁሉ ፡ በእሳት ፡ አቃጠሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ብሩንና ፡ ወርቁን ፡ የናሱንና ፡ የብረቱንም ፡ ዕቃ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ግምጃ ፡ ቤት ፡ አደረጉት ። ፳፭ ኢያሪኮን ፡ ሊሰልሉ ፡ ኢያሱ ፡ የሰደዳቸውንም ፡ መልክተኞች ፡ ስለ ፡ ሸሸገች ፡ ጋለሞታይቱን ፡ ረዓብን ÷ የአባትዋንም ፡ ቤተ ፡ ሰብ ÷ ያላትንም ፡ ሁሉ ፡ ኢያሱ ፡ አዳናቸው ፤ እርስዋም ፡ በእስራኤል ፡ መካከል ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ተቀምጣለች ።

፳፮ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኢያሱ ፡— ይህችን ፡ ከተማ ፡

ኢያሪኮን ፡ ለመሥራት ፡ የሚነሣ ፡ ሰው ፡ በእግ ዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፤ መሠረት ዋን ፡ ሲጀምር ፡ በኵር ፡ ልጁ ፡ ይጥፋ ፥ በርዋ ንም ፡ ሲያቆም ፡ ታናሹ ፡ ልጁ ፡ ይጥፋ ፡ ብሎ ፡ ማለ ። ፳፯ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ከኢያሱ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፤ ዝናውም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ወጣ ።

ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ እርም ፡ በሆነው ፡ ነገር ፡ በደሉ ፤ ከይሁዳ ፡ ነገድ ፡ የሆነ ፡ አካን ፥ እርሱም ፡ የከርሚ ፡ ልጅ ፥ የዘንበሪ ፡ ልጅ ፥ የዛራ ፡ ልጅ ፥ እርም ፡ ከሆነው ፡ ነገር ፡ ወሰደ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ነደደ ።

፪ ፡ ኢያሱም ፡ ከቤቴል ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ በቤትአዌን ፡ አጠገብ ፡ ወዳለችው ፡ ወደ ፡ ጋይ ፡ ሰዎችን ፡ ከኢያሪኮ ፡ ልኮ ፦ ውጡ ፡ ምድሪቱ ንም ፡ ሰልሉ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፤ ሰዎቹም ፡ ፫ ፡ ወጡ ፥ ጋይንም ፡ ሰለሉ ። ወደ ፡ ኢያሱም ፡ ተመልሰው ፦ ሁለት ፡ ወይም ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ያህል ፡ ሰው ፡ ወጥተው ፡ ጋይን ፡ ይምቱ ፡ እንጂ ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ አይውጣ ፤ ጥቂቶች ፡ ናቸውና ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ወደዚያ ፡ ለመሄድ ፡ ፬ ፡ አይድከም ፡ አሉት ። ሦስት ፡ ሺህ ፡ ያህል ፡ ሰዎ ችም ፡ ወደዚያ ፡ ወጡ ፡ ከጋይም ፡ ሰዎች ፡ ፊት ፡ ፭ ፡ ሸሹ ። የጋይም ፡ ሰዎች ፡ ከእነርሱ ፡ ሠላሳ ፡ ስድ ስት ፡ ያህል ፡ ሰዎችን ፡ መቱ ፤ ከበሩ ፡ እስከ ፡ ሽባሪም ፡ ድረስ ፡ አባረሩአቸው ፡ በቍልቍለ ቱም ፡ መቱአቸው ፤ የሕዝቡም ፡ ልብ ፡ ቀለጠ ፥ እንደ ፡ ውኃም ፡ ሆነ ።

፮ ፡ ኢያሱም ፡ ልብሱን ፡ ቀደደ ፥ እርሱና ፡ የእ ስራኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ በግምባራ ቸው ፡ ተደፉ ፤ በራሳቸውም ፡ ላይ ፡ ትቢያ ፡ ፯ ፡ ነሰነሱ ። ኢያሱም ፡ አለ ፦ ዋይ ! ጌታ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ በአሞራውያን ፡ እጅ ፡ አሳ ልፈህ ፡ ትሰጠን ፡ ታጠፋንም ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡ ሕዝብ ፡ ዮርዳኖስን ፡ ለምን ፡ አሻገርኸው ? በዮ ርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ መቀመጥን ፡ በወደድን ፡ ነበር ፡ ፰ ፡ እኮ ! ጌታ ፡ ሆይ ፥ እስራኤል ፡ በጠላቶቻቸው ፡ ፱ ፡ ፊት ፡ ከሸሹ ፡ ምን ፡ እላለሁ ? ከነዓናውያንም ፡ በምድሪቱም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ሰምተው ፡ ይከ ብቡናል ፥ ስማችንንም ፡ ከምድር ፡ ያጠፉሉ ፤ ለታላቁ ፡ ስምህም ፡ የምታደርገው ፡ ምንድር ፡ ነው ?

፲ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ኢያሱን ፡ አለው ፦ ለምን ፡ ፲፩ ፡ በግምባርህ ፡ ተደፍተሃል ? ቁም ፤ እስራኤል ፡ በድሎአል ፤ ያዘዝኋቸውንም ፡ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ አፍርሰዋል ፤ እርም ፡ የሆነውንም ፡ ነገር ፡ ወሰዱ ፥ ሰረቁም ፥ ዋሹም ፥ በዕቃቸውም ፡ ውስጥ ፡ ሸሸ ፲፪ ፡ ጉት ። ስለዚህም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በጠ ላቶቻቸው ፡ ፊት ፡ መቆም ፡ አይችሉም ፤ የተ ረገሙ ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ በጠላቶቻቸው ፡ ፊት ፡ ይሸ ሻሉ ፤ እርም ፡ የሆነውንም ፡ ነገር ፡ ከመካከላ ችሁ ፡ ካላጠፋችሁ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ አልሆንም ። ፲፫ ፡ ተነሣና ፡ ሕዝቡን ፡ ቀድስ ፥ እንዲህም ፡ በላቸው ፦ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ እርም ፡ የሆነ ፡ ነገር ፡ በመካከልህ ፡ አለ ፤ እር ምም ፡ የሆነውን ፡ ነገር ፡ ከመካከላችሁ ፡ እስክ ታጠፉ ፡ ድረስ ፡ በጠላቶቻችሁ ፡ ፊት ፡ መቆም ፡ አትችሉም ፡ ብሎ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ ተናግሮአልና ፡ እስከ ፡ ነገ ፡ ተቀደሱ ። ፲፬ ፡ ነገም ፡ በየነገዳችሁ ፡ ትቀርባላችሁ ፤ እግዚአ ብሔርም ፡ የሚለየው ፡ ነገድ ፡ በየወገኖቹ ፡ ይቀ ርባል ፤ እግዚአብሔርም ፡ የሚለየው ፡ ወገን ፡ በየቤተ ፡ ሰቦቹ ፡ ይቀርባል ፤ እግዚአብሔርም ፡ የሚለየው ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፡ በየሰዉ ፡ ይቀርባል ። ፲፭ ፡ እርም ፡ የሆነውም ፡ ነገር ፡ የተገኘበት ፡ ሰው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አፍርሶአልና ፥ በእስራኤልም ፡ ዘንድ ፡ በደል ፡ አድርጎአልና ፡ እርሱና ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ በእሳት ፡ ይቃጠላሉ ።

፲፮ ፡ ኢያሱም ፡ ማልዶ ፡ ተነሣ ፥ እስራኤልንም ፡ በየነገዶቻቸው ፡ አቀረበ ፤ የይሁዳም ፡ ነገድ ፡ ፲፯ ፡ ተለየ ፤ የይሁዳንም ፡ ወገን ፡ አቀረበ ፡ የዛራ ንም ፡ ወገን ፡ ለየ ፤ የዛራንም ፡ ወገን ፡ ሰዎች ፡ ፲፰ ፡ አቀረበ ፤ ዘንበሪም ፡ ተለየ ፤ የቤቱንም ፡ ሰዎች ፡ አቀረበ ፤ ከይሁዳም ፡ ነገድ ፡ የሆነ ፡ የከርሚ ፡ ልጅ ፡ የዘንበሪ ፡ ልጅ ፡ የዛራ ፡ ልጅ ፡ አካን ፡ ፲፱ ፡ ተለየ ። ኢያሱም ፡ አካንን ፦ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ ስጥ ፥ ለእርሱም ፡ ተናዘዝ ፤ ያደረግኸውንም ፡ ንገረኝ ፤ አትሸሽገኝ ፡ አለው ። ፳ ፡ አካንም ፡ መልሶ ፡ ኢያሱን ፦ በእውነት ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በድያለሁ ፡ እንዲህና ፡ እንዲ ፳፩ ፡ ህም ፡ አድርጌአለሁ ። በዘረፋ ፡ መካከል ፡ አንድ ፡ ያማረ ፡ የሰናዖር ፡ ካባ ፥ ሁለት ፡ መቶም ፡ ሰቅል ፡ ብር ፥ ሚዛኑም ፡ አምሳ ፡ ሰቅል ፡ የሆነ ፡ ወርቅ ፡ አይቼ ፡ ተመኘኋቸው ፥ ወሰድኋቸውም ፤ እነ ሆም ፥ በድንኳኔ ፡ ውስጥ ፡ በመሬት ፡ ተሸሽገ ዋል ፥ ብሩም ፡ ከሁሉ ፡ በታች ፡ ነው ፡ አለው ።

፳፪ ፡ ኢያሱም ፡ መልክተኞች ፡ ሰደደ ፡ ወደ ፡ ድን ኳኑም ፡ ሮጡ ፤ እነሆም ፥ በድንኳኑ ፡ ውስጥ ፡ ተሸ ፳፫ ፡ ሽጎ ፡ ነበር ፥ ብሩም ፡ በበታቹ ፡ ነበረ ። ከድን ኳኑም ፡ ውስጥ ፡ ወስደው ፡ ወደ ፡ ኢያሱና ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ አመጡት ፤ በእግ ፳፬ ፡ ዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ አኖሩት ። ኢያሱና ፡ እስ ራኤል ፡ ሁሉ ፡ የዛራን ፡ ልጅ ፡ አካንን ፥ ብሩ ንም ፥ ካባውንም ፥ ወርቁንም ፥ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቹንም ፥ በሬዎቹንም ፥ አህያዎቹ ንም ፥ በጎቹንም ፥ ድንኳኑንም ፥ ያለውንም ፡ ሁሉ ፡ ወስደው ፡ ወደ ፡ አኮር ፡ ሸለቆ ፡ አመጡ ፳፭ ፡ አቸው ። ኢያሱም ፦ ለምን ፡ አስጨነቅኸን ? እግዚአብሔር ፡ ዛሬ ፡ ያስጨንቅሃል ፡ አለው ፤ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ በድንጋይ ፡ ወገሩት ፤ በእ ሳትም ፡ አቃጠሉአቸው ፥ በድንጋይም ፡ ወገሩ ፳፮ ፡ አቸው ። በላዩም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ያለ ፡ ታላቅ ፡ የድንጋይ ፡ ክምር ፡ ከመሩ ፤ እግዚአብ ሔርም ፡ ከቍጣው ፡ ትኵሳት ፡ ተመለሰ ። ስለ

ዚህም ፡ የዚያ ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ የአኮር ፡ ሸለቆ ፡ ተብሎ ፡ ተጠራ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ኢያሱን ፦ አትፍራ ፥ አትደንግጥ ፤ ሰልፈኞችን ፡ ሁሉ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ውሰድ ፥ ተነሥተህም ፡ ወደ ፡ ጋይ ፡ ውጣ ፤ እይ ፥ የጋይን ፡ ንጉሥ ፡ ሕዝቡንም ፡ ከተማውንም ፡ ምድሩንም ፡ በእጅህ ፡ ሰጥቼሃለሁ ። ፪ በኢያሪኮና ፡ በንጉሥዋም ፡ እንዳደረግህ ፡ እንዲሁ ፡ በጋይና ፡ በንጉሥዋ ፡ ታደርጋለህ ፤ ምርኮዋንና ፡ ከብትዋን ፡ ግን ፡ ለራሳችሁ ፡ ትዘርፋላችሁ ፤ ከከተማይቱም ፡ በስተ ፡ ኋላ ፡ ድብቅ ፡ ጦር ፡ አስቀምጥ ፡ አለው ።

፫ ኢያሱም ፡ ሰልፈኞቹም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ጋይ ፡ ሊወጡ ፡ ተነሡ ፤ ኢያሱም ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡ የሆኑትን ፡ ሠላሳ ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ መረጠ ፡ በሌሊትም ፡ ሰደዳቸው ። ፬ እንዲህም ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ፦ እነሆ ፥ ከከተማይቱ ፡ በስተ ፡ ኋላ ፡ ተደበቁ ፤ ከከተማይቱ ፡ አትራቁ ፥ ሁላችሁም ፡ ተዘጋጁ ፤ ፭ እኔ ፡ ከእኔም ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ እንቀርባለን ፤ እኛንም ፡ ሊገናኙ ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፡ ከፊታቸው ፡ እንሸሻለን ፤ ፮ አስቀድመን ፡ እንደ ፡ ሸሸን ፡ የምንሸሽ ፡ ይመስላቸዋልና ፡ ከከተማይቱ ፡ እስክናርቃቸው ፡ ድረስ ፡ ወጥተው ፡ ይከተሉናል ፤ እኛም ፡ ከፊታቸው ፡ እንሸሻለን ። ፯ እናንተም ፡ ከተደበቃችሁበት ፡ ስፍራ ፡ ተነሡ ፤ አምላካችሁም ፡ እግዚአብሔር ፡ እርስዋን ፡ በእጃችሁ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣልና ፡ ከተማይቱን ፡ ያዙ ። ፰ በያዛችኋትም ፡ ጊዜ ፡ ከተማይቱን ፡ በእሳት ፡ አቃጥሉአት ፤ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ አድርጉ ፤ እነሆ ፥ አዝዣችኋለሁ ። ፱ ኢያሱም ፡ ሰደዳቸው ፤ ወደሚደበቁበትም ፡ ስፍራ ፡ ሄዱ ፥ በጋይና ፡ በቤቴል ፡ መካከልም ፡ በጋይ ፡ በምዕራብ ፡ በኩል ፡ ተቀመጡ ፤ ኢያሱ ፡ ግን ፡ በዚያች ፡ ሌሊት ፡ በሕዝቡ ፡ መካከል ፡ አደረ ።

፲ ኢያሱም ፡ ማልዶ ፡ ተነሣ ፥ ሕዝቡንም ፡ አሰለፈ ፤ እርሱም ፡ የእስራኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ፲፩ ከሕዝቡ ፡ በፊት ፡ ወደ ፡ ጋይ ፡ ወጡ ። ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩ ፡ ሰልፈኞች ፡ ሁሉ ፡ ወጥተው ፡ ቀረቡ ፥ ወደ ፡ ከተማይቱም ፡ ፊት ፡ ደረሱ ፥ በጋይም ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ሰፈሩ ፤ በእነርሱና ፡ በጋይም ፡ መካከል ፡ ሸለቆ ፡ ነበረ ። ፲፪ አምስት ፡ ሺህ ፡ ያህል ፡ ሰዎችንም ፡ ወስዶ ፡ በቤቴልና ፡ በጋይ ፡ መካከል ፡ በከተማይቱም ፡ በምዕራብ ፡ በኩል ፡ ደብቆ ፡ አስቀመጣቸው ። ፲፫ በከተማይቱ ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ የነበሩትን ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ በከተማይቱም ፡ በምዕራብ ፡ በኩል ፡ የተደበቁትን ፡ ሕዝብ ፡ አኖሩ ፤ ኢያሱም ፡ በዚያች ፡ ሌሊት ፡ ወደ ፡ ሸለቆው ፡ መካከል ፡ ሄደ ። ፲፬ የጋይም ፡ ንጉሥ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ የከተማይቱ ፡ ሰዎች ፡ ቸኰለው ፡ በማለዳ ፡ ተነሡ ፤ እርሱና ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በተወሰነው ፡ ጊዜ ፡ በዓረባ ፡ ፊት ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ ስፍራ ፡ እስራኤልን ፡ በሰልፍ ፡ ለመገናኘት ፡ ወጡ ፤ ከከተማይቱ ፡ በስተ ፡ ኋላ ፡ ግን ፡ ድብቅ ፡ ጦር ፡ እንዳለ ፡ አያውቅም ፡ ነበር ። ፲፭ ኢያሱም ፡ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ድል ፡ የተነሡ ፡ መስለው ፡ ከፊታቸው ፡ በምድረ ፡ በዳው ፡ መንገድ ፡ ሸሹ ። ፲፮ በከተማይቱም ፡ የነበሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ሊያሳድዱአቸው ፡ ተጠሩ ፤ ኢያሱንም ፡ አሳደዱት ፥ ፲፯ ከከተማይቱም ፡ እንዲርቁ ፡ አደረጓቸው ። በጋይና ፡ በቤቴልም ፡ ውስጥ ፡ እስራኤልን ፡ ለማሳደድ ፡ ያልወጣ ፡ ሰው ፡ አልነበረም ፤ ከተማይቱንም ፡ ከፍተው ፡ ተዉ ፥ እስራኤልንም ፡ አሳደዱት ።

፲፰ እግዚአብሔር ፡ ኢያሱን ፦ ጋይን ፡ በእጅህ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጥሃለሁና ፡ በእጅህ ፡ ያለውን ፡ ጦር ፡ በላይዋ ፡ ዘርጋ ፡ አለው ፤ ኢያሱም ፡ በእጁ ፡ ያለውን ፡ ጦር ፡ በከተማይቱ ፡ ላይ ፡ ዘረጋ ። ፲፱ የተደበቁትም ፡ ፈጥነው ፡ ከስፍራቸው ፡ ተነሡ ፥ ኢያሱም ፡ እጁን ፡ በዘረጋ ፡ ጊዜ ፡ ሮጡ ፥ ወደ ፡ ከተማይቱም ፡ ገብተው ፡ ያዙአት ፤ ፈጥነውም ፡ ከተማይቱን ፡ በእሳት ፡ አቃጠሉአት ። ፳ የጋይም ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ዞረው ፡ የከተማይቱ ፡ ጢስ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ሲወጣ ፡ አዩ ፥ ወዲህና ፡ ወዲያም ፡ መሸሽ ፡ አልቻሉም ፤ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳም ፡ የሸሹ ፡ ሕዝብ ፡ በሚያሳድዱአቸው ፡ ላይ ፡ ተመለሱ ። ፳፩ ኢያሱም ፡ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ተደብቀው ፡ የነበሩት ፡ ከተማይቱን ፡ እንደ ፡ ያዙ ፥ የከተማይቱም ፡ ጢስ ፡ እንደ ፡ ተነሣ ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ተመልሰው ፡ የጋይን ፡ ሰዎች ፡ ገደሉ ። ፳፪ ሌሎቹም ፡ በላያቸው ፡ ከከተማይቱ ፡ ወጡ ፤ የጋይም ፡ ሰዎች ፡ በእስራኤል ፡ መካከል ፡ ሆኑ ፥ እስራኤልም ፡ ከበቡአቸው ፤ አንድ ፡ እንኳ ፡ ሳይቀር ፡ ሳያመልጥም ፡ ገደሉአቸው ። ፳፫ የጋይንም ፡ ንጉሥ ፡ ሳይሞት ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ኢያሱ ፡ አመጡት ።

፳፬ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ እስራኤልን ፡ ሊያሳድዱ ፡ ሄደው ፡ የነበሩትን ፡ የጋይን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በሜዳና ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ከገደሉአቸው ፡ በኋላ ፥ እነርሱም ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ እስኪያልቁ ፡ ድረስ ፡ ከወደቁ ፡ በኋላ ፥ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ጋይ ፡ ተመለሱ ፥ በሰይፍም ፡ ስለት ፡ መቱአት ። ፳፭ በዚያም ፡ ቀን ፡ የወደቁት ፡ ሁሉ ፡ ወንድም ፡ ሴትም ፡ የጋይ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ነፍስ ፡ ነበሩ ። ፳፮ ኢያሱም ፡ በጋይ ፡ የሚኖሩትን ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሞ ፡ እስኪያጠፉ ፡ ድረስ ፡ ጦር ፡ የዘረጋበትን ፡ እጁን ፡ አላጠፈም ። ፳፯ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ኢያሱን ፡ እንዳዘዘው ፡ ቃል ፡ የዚያችን ፡ ከተማ ፡ ከብትና ፡ ምርኮ ፡ እስራኤል ፡ ለራሳቸው ፡ ዘረፉ ። ፳፰ ኢያሱም ፡ ጋይን ፡ አቃጠላት ፥ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ ድብድብና ፡ በረሃ ፡ ለዘላለም ፡ አደረጋት ። ፳፱ የጋይንም ፡ ንጉሥ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ በዛፍ ፡ ላይ ፡ ሰቀለው ፤ ፀሐይም ፡ በገባች ፡ ጊዜ ፡ ኢያሱ ፡ አዘዘ ፥ ሬሳውንም ፡ ከዛፍ ፡ አወረዱት ፥ በከተ

ማይቱም ፡ በር ፡ አደባበይ ፡ ጣሉት ፥ በላዩም ፡
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ያለውን ፡ ታላቅ ፡ የድን
ጋይ ፡ ክምር ፡ ከመሩበት ።

፴ ፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኢያሱ ፡ በጌባል ፡ ተራራ ፡
ላይ ፡ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
፴፩ ፡ መሠዊያን ፡ ሠራ ። የእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡
ሙሴ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እንዳዘዘ ፥ በሙ
ሴም ፡ ሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ እንደ ፡ ተጻፈው ፥ መሠዊ
ያው ፡ ካልተወቀረና ፡ ብረት ፡ ካልነካው ፡ ድን
ጋይ ፡ ነበረ ፤ በእርሱም ፡ ላይ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረቡ ፥ የደኅ
፴፪ ፡ ንነትንም ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዉ ። የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ ሲያዩ ፡ በዚያ ፡ ስፍራ ፡ በድንጋዮቹ ፡
፴፫ ፡ ላይ ፡ የሙሴን ፡ ሕግ ፡ ጻፈባቸው ። የእስራኤ
ልንም ፡ ሕዝብ ፡ አስቀድሞ ፡ ይባርኩ ፡ ዘንድ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ እንዳዘዘ ፥ እስ
ራኤል ፡ ሁሉ ፥ ሽማግሌዎቻቸውም ፥ አለቆቻቸ
ውም ፥ ፈራጆቻቸውም ፥ የአገሩ ፡ ልጆችም ፥
መጻተኞችም ፥ እኩሌቶቹ ፡ በገሪዛን ፡ ተራራ ፡
ፊት ፡ እኩሌቶቹም ፡ በጌባል ፡ ተራራ ፡ ፊት ፡
ሆነው ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
ታቦት ፡ በተሸከሙት ፡ በሌዋውያን ፡ ካህናት ፡
ፊት ፡ ለፊት ፥ በታቦቱም ፡ ፊት ፡ በወዲህና ፡
፴፬ ፡ በወዲያ ፡ ቆመው ፡ ነበር ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡
በሕጉ ፡ መጽሐፍ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ሁሉ ፥ የሕ
ጉን ፡ ቃሎች ፡ ሁሉ ፡ በረከቱንና ፡ እርግማኑን ፡
፴፭ ፡ አነበበ ። ኢያሱም ፡ በእስራኤል ፡ ጉባኤ ፡
ሁሉ ፡ በሴቶቹም ፡ በሕፃናቱም ፡ በመካከላቸ
ውም ፡ በሚኖሩት ፡ መጻተኞች ፡ ፊት ፡ ሁሉን ፡
አነበበ ፡ እንጂ ፡ ሙሴ ፡ ካዘዘው ፡ አንዲት ፡
ቃል ፡ አላስቀረም ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ፡ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በተራራ
ማው ፡ በቈላውም ፡ በታላቁ ፡ ባሕር ፡ ዳር ፡ በሊ
ባኖስም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ የነበሩ ፡ ነገሥታት ፡
ሁሉ ፥ ኬጢያዊ ፡ አሞራዊም ፡ ከነዓናዊም ፡
ፌርዛዊም ፡ ኤዊያዊም ፡ ኢያቡሳዊም ፥ ይህን ፡
፪ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፥ ኢያሱንና ፡ እስራኤልን ፡ ሊወጉ ፡
አንድ ፡ ሆነው ፡ ተሰበሰቡ ።

፫ ፡ የገባዖን ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ኢያሱ ፡ በኢያሪኮና ፡
፬ ፡ በጋይ ፡ ያደረገውን ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፥ እነርሱ ፡
ደግሞ ፡ ተንኰል ፡ አደረጉ ፤ ለራሳቸውም ፡
ስንቅ ፡ ያዙ ፥ በአህዮቻቸውም ፡ ላይ ፡ አሮጌ ፡
ዓይበትና ፡ ያረጀና ፡ የተቀደደ ፡ የተጠቀመም ፡
፭ ፡ የጠጅ ፡ አቁማዳ ፡ ጫኑ ። ያረጀ ፡ የተጠቀመም ፡
ጫማ ፡ በእግራቸው ፡ አደረጉ ፡ አሮጌም ፡ ልብስ ፡
ለበሱ ፤ ለስንቅም ፡ የያዙት ፡ እንጀራ ፡ ሁሉ ፡
፮ ፡ የደረቀና ፡ የሻገተ ፡ ነበረ ። ኢያሱም ፡ ወደ ፡
ሰፈረበት ፡ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ ሄደው ፡ ለእርሱና ፡
ለእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ — ከሩቅ ፡ አገር ፡ መጥተ
ናል ፤ አሁንም ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ኪዳን ፡ አድርጉ ፡
፯ ፡ አሉ ። የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ኤዊያውያ
ንን ፡ — ምናልባት ፡ በመካከላችን ፡ የምትቀ
መጡ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንዴትስ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡
፰ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ እናደርጋለን ? አሉአቸው ። ኢያሱ
ንም ፡ — እኛ ፡ ባሪያዎችህ ፡ ነን ፡ አሉት ። ኢያ
ሱም ፡ — እናንተ ፡ እነማን ፡ ናችሁ ? ከወዴትስ ፡
፱ ፡ መጣችሁ ? አላቸው ። እነርሱም ፡ አሉት ፡ — ከአ
ምላክህ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የተነሣ ፡
እጅግ ፡ ከራቀ ፡ አገር ፡ ባሪያዎችህ ፡ መጥተናል ፤
ዝናውንም ፥ በግብፅም ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፥
፲ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶም ፡ በነበሩት ፡ በሁለቱ ፡ በአ
ሞራውያን ፡ ነገሥታት ፡ በሐሴቦን ፡ ንጉሥ ፡
በሴዎን ፡ በአስታሮትም ፡ በነበረው ፡ በባሳን ፡
ንጉሥ ፡ በዐግ ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፡ ሰምተናል ።
፲፩ ፡ ሽማግሌዎቻችንም ፡ በምድራችንም ፡ የሚኖ
ሩት ፡ ሁሉ ፡ — ለመንገድ ፡ ስንቅ ፡ በእጃችሁ ፡
ያዙ ፥ ልትገናኙአቸውም ፡ ሂዱ ፡ — እኛ ፡ ባሪያ
ዎቻችሁ ፡ ነን ፤ አሁንም ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ቃል ፡
፲፪ ፡ ኪዳን ፡ አድርጉ ፡ በሉአቸው ፡ አሉን ። ወደ ፡
እናንተ ፡ ለመምጣት ፡ በተነሣንበት ፡ ቀን ፡
ይህን ፡ እንጀራ ፡ ትኩሱን ፡ ለስንቅ ፡ ከቤታችን ፡
ወሰድነው ፤ አሁንም ፡ እነሆ ፥ ደርቆአል ፥ ሻግ
፲፫ ፡ ቶአልም ። እነዚህም ፡ የጠጅ ፡ አቁማዳዎች ፡
አዲስ ፡ ሳሉ ፡ ሞላንባቸው ፤ እነሆም ፥ ተቀድደ
ዋል ፤ መንገዳችንም ፡ እጅግ ፡ ስለ ፡ ራቀብን ፡
እነዚህ ፡ ልብሶቻችንና ፡ ጫማዎቻችን ፡ አርጅ
፲፬ ፡ ተዋል ። ሰዎቹም ፡ ከስንቃቸው ፡ ወሰዱ ፥ እግ
፲፭ ፡ ዚአብሔርንም ፡ አልጠየቁም ። ኢያሱም ፡ ከእነ
ርሱ ፡ ጋር ፡ ሰላም ፡ አደረገ ፥ በሕይወት ፡ እንዲ
ተዋቸውም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደ
ረገ ፤ የማኅበሩም ፡ አለቆች ፡ ማሉላቸው ።

፲፮ ፡ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ካደረጉ ፡ ከሦ
ስት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ጎረቤቶቻቸው ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡
፲፯ ፡ በመካከላቸውም ፡ እንደ ፡ ኖሩ ፡ ሰሙ ። የእስራ
ኤልም ፡ ልጆች ፡ ተጕዘው ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡
ወደ ፡ ከተሞቻቸው ፡ መጡ ፤ የከተሞቻቸውም ፡
ስም ፡ ገባዖን ፥ ከፊራ ፥ ብኤሮት ፥ ቂርያትይዓሪም ፡
፲፰ ፡ ነበረ ። የሕዝቡም ፡ አለቆች ፡ በእስራኤል ፡
አምላክ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ማሉላቸው ፡
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ አልመቱአቸውም ። ማኅበ
፲፱ ፡ ሩም ፡ ሁሉ ፡ በአለቆቹ ፡ ላይ ፡ አጕረመረመ ። አለ
ቆቹም ፡ ሁሉ ፡ ለማኅበሩ ፡ ሁሉ ፡ — በእስራኤል ፡
አምላክ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ምለንላቸዋል ፤ ስለ
ዚህም ፡ እንነካቸው ፡ ዘንድ ፡ አይገባንም ።
፳ ፡ ስለ ፡ ማልንላቸው ፡ መሐላ ፡ ቍጣ ፡ እንዳይወር
ድብን ፡ ይህን ፡ እናድርግባቸው ፥ በሕይወትም ፡
፳፩ ፡ እንተዋቸው ፡ አሉአቸው ። አለቆቹም ፡ — በሕ
ይወት ፡ ይኑሩ ፡ አሉአቸው ፤ አለቆቹም ፡ እንደ ፡
ተናገሩአቸው ፡ ለማኅበሩ ፡ ሁሉ ፡ እንጨት ፡
ቆራጮች ፡ ውኃም ፡ ቀጂዎች ፡ ሆኑ ።

፳፪ ፡ ኢያሱም ፡ ጠርቶ ፡ — እናንተ ፡ በመካከላችን ፡
ስትኖሩ ፡ — ከእናንተ ፡ እጅግ ፡ የራቅን ፡ ነን ፡
፳፫ ፡ ብላችሁ ፡ ለምን ፡ አታለላችሁን ? አሁንም ፡ የተ
ረገማችሁ ፡ ናችሁ ፤ ለአምላኬም ፡ ቤት ፡ እን
ጨት ፡ ቈራጭ ፡ ውኃም ፡ ቀጂ ፡ የሆነ ፡ ባሪያ ፡
ከእናንተ ፡ ለዘላለም ፡ አይጠፋም ፡ አላቸው ።

፳፬ መልሰውም ፡ ኢያሱን ፡ — እኛ ፡ ባሪያዎችህ ፡ ምድሪቱን ፡ ሁሉ ፡ ይሰጣችሁ ፡ ዘንድ ÷ በእርስዋም ፡ የሚኖሩትን ፡ ሁሉ ፡ ከፊታችሁ ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ባሪያውን ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘ ፡ በእውነት ፡ ሰምተናል ÷ ስለዚህም ፡ ከእናንተ ፡ የተነሣ ፡ ስለ ፡ ነፍሳችን ፡ እጅግ ፡ ፈራን ÷ ይህንንም ፡ ነገር ፡ አድርገናል ። ፳፭ አሁንም ÷ እነሆ ÷ በእጅህ ፡ ውስጥ ፡ ነን ፤ ለዓይንህም ፡ መልካምና ፡ ቅን ፡ የመሰለውን ፡ ነገር ፡ አድርግብን ፡ አሉት ። ፳፮ እንዲሁም ፡ አደረገባቸው ÷ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ አዳናቸው ÷ አልገደሉአቸውምም ። ፳፯ በዚያም ፡ ቀን ፡ ኢያሱ ፡ ለማኅበሩ ፡ በመረጠውም ፡ ስፍራ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ እንጨት ፡ ቈራጮች ፡ ውኃም ፡ ቀጂዎች ፡ አደረጋቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ የኢየሩሳሌም ፡ ንጉሥ ፡ አዶኒጼዴቅ ፡ ኢያሱ ፡ ጋይን ፡ እንደ ፡ ያዘ ፡ ፈጽሞም ፡ እንዳጠፋት ÷ በኢያሪኮና ፡ በንጉሥዋም ፡ ያደረገውን ፡ እንዲሁ ፡ በጋይና ፡ በንጉሥዋ ፡ እንዳደረገ ÷ የገባዖንም ፡ ሰዎች ፡ ከእስራኤል ፡ ጋር ፡ ሰላም ፡ እንዳደረጉ ፡ በመካከላቸውም ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ÷ ፪ ገባዖን ፡ ከመንግሥታት ፡ ከተሞች ፡ እንደ ፡ አንዲቱ ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ፡ ስለ ፡ ሆነች ÷ ከጋይም ፡ ስለ ፡ በለጠች ÷ ሰዎችዋም ፡ ሁሉ ፡ ኃያላን ፡ ስለ ፡ ነበሩ ÷ እጅግ ፡ ፈራ ። ፫ ስለዚህም ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ንጉሥ ፡ አዶኒጼዴቅ ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ሆሃም ÷ ወደ ፡ የርሙት ፡ ንጉሥም ፡ ወደ ፡ ፒርአም ÷ ወደ ፡ ለኪሶ ፡ ንጉሥም ፡ ወደ ፡ ያፊዓ ÷ ወደ ፡ አዶላም ፡ ንጉሥም ፡ ወደ ፡ ዳቤር ፡ ልኮ ፡— ፬ ወደ ፡ እኔ ፡ ውጡ ÷ ከኢያሱና ፡ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ ሰላም ፡ አድርገዋልና ፡ ገባዖንን ፡ ለመምታት ፡ እግዙኝ ፡ አለ ። ፭ አምስቱም ፡ የአሞራውያን ፡ ነገሥታት ÷ የኢየሩሳሌም ፡ ንጉሥ ÷ የኬብሮን ፡ ንጉሥ ÷ የየርሙት ፡ ንጉሥ ÷ የለኪሶ ፡ ንጉሥ ÷ የአዶላም ፡ ንጉሥ ÷ ከሠራዊቶቻቸው ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ተሰብስበው ፡ ወጡ ÷ ከገባዖንም ፡ ጋር ፡ ሊጋጠሙ ፡ ከበቡአት ።

፮ የገባዖንም ፡ ሰዎች ፡ ኢያሱ ፡ ወደ ፡ ሰፈረበት ፡ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ ልከው ፡ — ባሪያዎችህን ፡ ለመርዳት ፡ እጅህን ፡ አትመልስ ፤ በተራራማው ፡ አገር ፡ የሚኖሩ ፡ የአሞራውያን ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ ተሰብስበውብናልና ፡ ፈጥነህ ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ ውጣ ፡ አድነንም ፡ እርዳንም ፡ አሉት ። ፯ ኢያሱም ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩ ፡ ሰልፈኞች ፡ ሁሉ ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላኑም ፡ ሁሉ ፡ ከጌልገላ ፡ ወጡ ። ፰ እግዚአብሔርም ፡ ኢያሱን ፡— በእጅህ ፡ አሳልፌ ፡ ሰጥቼአቸዋለሁና ፡ አትፍራቸው ፤ ከእነርሱም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ የሚቋቋምህ ፡ የለም ፡ አለው ። ፱ ኢያሱም ፡ ከጌልገላ ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ ገሥግሦ ፡ በድንገት ፡ መጣባቸው ። ፲ እግዚአብሔርም ፡ በእስራኤል ፡ ፊት ፡ አስደነገጣቸው ፤ በገባዖንም ፡ ታላቅ ፡ መምታት ፡ መታቻው ÷ በቤትሖሮንም ፡ ዐቀበት ፡ በመንገድ ፡ አሳደዳቸው ÷ እስከ ፡ ዓዜቃና ፡ እስከ ፡ መቄዳ ፡ ድረስ ፡ መታቸው ። ፲፩ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ እየሸሹ ፡ በቤትሖሮን ፡ ቍልቍለት ፡ ሲወርዱ ÷ ወደ ፡ ዓዜቃ ፡ እስኪደርሱ ፡ ድረስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሰማይ ፡ ታላላቅ ፡ የበረዶ ፡ ድንጋይ ፡ አወረደባቸውና ፡ ሞቱ ፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በሰይፍ ፡ ከገደሉአቸው ፡ ይልቅ ፡ በበረዶ ፡ ድንጋይ ፡ የሞቱት ፡ በለጡ ።

፲፪ እግዚአብሔርም ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ አሞራውያንን ፡ አሳልፎ ፡ በሰጠ ፡ ቀን ፡ ኢያሱ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተናገረ ፤ በእስራኤልም ፡ ፊት ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— በገባዖን ፡ ላይ ፡ ፀሐይ ፡ ትቁም ÷ በኤሎንም ፡ ሸለቆ ፡ ጨረቃ ፤ ፲፫ ሕዝቡም ፡ ጠላቶቻቸውን ፡ እስኪበቀሉ ፡ ድረስ ፡ ፀሐይ ፡ ቆመ ÷ ጨረቃም ፡ ዘገየ ። ይህስ ፡ በያሻር ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ፀሐይም ፡ በሰማይ ፡ መካከል ፡ ዘገየ ÷ አንድ ፡ ቀንም ፡ ሙሉ ፡ ያህል ፡ ለመግባት ፡ አልቸኰለም ። ፲፬ እግዚአብሔር ፡ ለእስራኤል ፡ ይዋጋ ፡ ነበርና ፡ እግዚአብሔር ፡ የሰውን ፡ ቃል ፡ የሰማበት ፡ እንደ ፡ ዚያ ፡ ያለ ፡ ቀን ፡ ከዚያም ፡ በፊት ፡ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ አልነበረም ።

፲፭ ኢያሱም ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ሰፈራቸው ፡ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ ተመለሱ ።

፲፮ እነዚህም ፡ አምስት ፡ ነገሥታት ፡ ሸሽተው ፡ በመቄዳ ፡ ዋሻ ፡ ተሸሸጉ ። ፲፯ ለኢያሱም ፡— አምስቱ ፡ ነገሥታት ፡ በመቄዳ ፡ ዋሻ ፡ ተሸሽገው ፡ ተገኙ ፡ ብለው ፡ ነገሩት ። ፲፰ ኢያሱም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ወደ ፡ ዋሻው ፡ አፍ ፡ ታላላቅ ፡ ድንጋይ ፡ አንከባልላችሁ ÷ ይጠብቁአቸው ፡ ዘንድ ፡ ሰዎችን ፡ በዚያ ፡ አኑሩ ፤ ፲፱ እናንተ ፡ ግን ፡ አትዘግዩ ÷ ጠላቶቻችሁንም ፡ አባርሩአቸው ÷ በኋላም ፡ ያሉትን ፡ ግደሉ ፤ አምላካችሁም ፡ እግዚአብሔር ፡ በእጃችሁ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶአችዋልና ፡ ወደ ፡ ከተሞቻቸው ፡ እንዳይገቡ ፡ ከልክሉአቸው ፡ አለ ። ፳ እስኪጠፉም ፡ ድረስ ፡ ኢያሱና ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በታላቅ ፡ መምታት ፡ መምታታቸውን ፡ በፈጸሙ ፡ ጊዜ ÷ ከእነርሱም ፡ ያመለጡት ፡ ወደ ፡ ተመሸገ ፡ ከተማ ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ÷ ፳፩ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ኢያሱ ፡ ወደ ፡ ሰፈረበት ፡ ወደ ፡ መቄዳ ፡ በደኅና ፡ ተመለሱ ፤ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ምላሱን ፡ ማንቀሳቀስ ፡ የደፈረ ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ የለም ።

፳፪ ኢያሱም ፡— የዋሻውን ፡ አፍ ፡ ክፈቱ ÷ እነዚያንም ፡ አምስት ፡ ነገሥታት ፡ ከዋሻው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አውጡአቸው ፡ አለ ። ፳፫ እንዲህም ፡ አደረጉ ፤ አምስቱንም ፡ ነገሥታት ÷ የኢየሩሳሌምን ፡ ንጉሥ ፡ የኬብሮንንም ፡ ንጉሥ ፡ የየርሙትንም ፡ ንጉሥ ፡ የለኪሶንም ፡ ንጉሥ ፡ የአዶላምንም ፡ ንጉሥ ÷ ከዋሻው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አወጡአቸው ። ፳፬ እነዚያንም ፡ ነገሥታት ፡ ወደ ፡

ኢያሱ፡በወጡአቸው፡ጊዜ፡ኢያሱ፡የእስራኤ
ልን፡ሰዎች፡ሁሉ፡ጠራ፥ከእርሱም፡ጋር፡የሄ
ዱትን፡የሰልፈኞች፡አለቆች፡— ቅረቡ፥በእነ
ዚህም፡ነገሥታት፡አንገት፡ላይ፡እግራችሁን፡
አኑሩ፡አላቸው ። ቀረቡም፡በአንገታቸውም፡
፳፭ ላይ፡እግራቸውን፡አኖሩ ። ኢያሱም፡— እግ
ዚአብሔር፡በምትወጉአቸው፡በጠላቶቻችሁ፡
ሁሉ፡ላይ፡እንዲሁ፡ያደርጋልና፡አትፍሩ፥
አትደንግጡ ፤ ጽኑ፥አይዞአችሁ፡አላቸው ።
፳፮ ከዚህም፡በኋላ፡መትተው፡ገደሉአቸው፥በአ
ምስቱም፡ዛፎች፡ላይ፡ሰቀሉአቸው ፤ እስከ፡
ማታም፡ድረስ፡በዛፎቹ፡ተሰቅለው፡ቈዩ ።
፳፯ ፀሐይም፡ልትገባ፡በቀረበች፡ጊዜ፡ኢያሱ፡
አዘዘ፥ከዛፎችም፡አወረዱአቸው፥ተሸሽገ
ውም፡በነበሩበት፡ዋሻ፡ጣሉአቸው፥እስከ፡
ዛሬም፡ድረስ፡በዋሻው፡አፍ፡ታላላቅ፡ድን
ጋይ፡ተደርጎአል ።

፳፰ በዚያም፡ቀን፡ኢያሱ፡መቄዳን፡ያዛት፥
እርስዋንና፡ንጉሥዋንም፡በሰይፍ፡ስለት፡
መታ፤በእርስዋም፡ያሉትን፡ነፍሳት፡ሁሉ፡
ፈጽሞ፡አጠፋቸው፥ከእነርሱም፡አንዱን፡
ስንኳ፡አላስቀረም ፤ በኢያሪኮም፡ንጉሥ፡እን
ዳደረገ፡በመቄዳ፡ንጉሥ፡አደረገ ።

፳፱ ኢያሱም፡ከእርሱም፡ጋር፡እስራኤል፡ሁሉ፡
ከመቄዳ፡ወደ፡ልብና፡አለፉ፥ልብናንም፡
፴ ወጉ ። እግዚአብሔርም፡እርስዋንና፡ንጉሥ
ዋን፡በእስራኤል፡እጅ፡አሳልፎ፡ሰጠ ፤ እር
ስዋንም፡በእርስዋም፡ያሉትን፡ነፍሳት፡ሁሉ፡
በሰይፍ፡ስለት፡መታ፥በእርስዋም፡አንዱን፡
ስንኳ፡አላስቀረም ፤ በኢያሪኮም፡ንጉሥ፡እን
ዳደረገው፡በልብና፡ንጉሥ፡አደረገ ።

፴፩ ኢያሱም፡ከእርሱም፡ጋር፡እስራኤል፡ሁሉ፡
ከልብና፡ወደ፡ለኪሶ፡አለፉ፥ከበቡአትም፥
፴፪ ወጉአትም ። እግዚአብሔርም፡ለኪሶን፡በእ
ስራኤል፡እጅ፡አሳልፎ፡ሰጣት፥በሁለተኛ
ውም፡ቀን፡ያዙአት ፤ በልብናም፡እንዳደረ
ጉት፡ሁሉ፥እርስዋን፡በእርስዋም፡ያሉትን፡
ነፍሳት፡ሁሉ፡በሰይፍ፡ስለት፡መቱአቸው ።

፴፫ በዚያን፡ጊዜም፡የጌዝር፡ንጉሥ፡ሆራም፡
ለኪሶን፡ለመርዳት፡ወጣ፤ኢያሱም፡አንድ፡
ስንኳ፡ሳይቀር፡እርሱንና፡ሕዝቡን፡መታ ።

፴፬ ኢያሱም፡ከእርሱም፡ጋር፡እስራኤል፡ሁሉ፡
ከለኪሶ፡ወደ፡አዶላም፡አለፉ፥ከበቡአትም፥
፴፭ ወጉአትም ፤ በዚያም፡ቀን፡ያዙአት፥በሰይ
ፍም፡ስለት፡መቱአት ፤ በለኪሶም፡እንዳደረ
ገው፡ሁሉ፥በእርስዋ፡ያሉትን፡ነፍሳት፡
ሁሉ፡በዚያ፡ቀን፡ፈጽሞ፡አጠፋ ።

፴፮ ኢያሱም፡ከእርሱም፡ጋር፡እስራኤል፡ሁሉ፡
ከአዶላም፡ወደ፡ኬብሮን፡ወጡ፥ወጉአትም፥
፴፯ ያዙአትም ፤ እርስዋንም፡ንጉሥዋንም፡ከተሞ
ችዋንም፡ሁሉ፡በእርስዋም፡ያሉትን፡ነፍ
ሳት፡ሁሉ፡በሰይፍ፡ስለት፡መቱ ፤ በአዶላም፡
እንዳደረገው፡ሁሉ፡ማንንም፡አላስቀረም ፤
እርስዋንም፡በእርስዋም፡ያሉትን፡ነፍሳት፡
ሁሉ፡ፈጽሞ፡አጠፋ ።

፴፰ ኢያሱም፡ከእርሱም፡ጋር፡እስራኤል፡ሁሉ፡
፴፱ ወደ፡ዳቤር፡ተመለሱ፥ወጉአትም፥እርስዋ
ንም፡ንጉሥዋንም፡ከተሞችዋንም፡ያዙ ፤ በሰ
ይፍም፡ስለት፡መቱአቸው፥በእነርሱም፡
ውስጥ፡ያሉትን፡ነፍሳት፡ሁሉ፡ፈጽመው፡
አጠፉ ፤ ማንንም፡አላስቀረም ፤ በኬብሮን፥
ደግሞ፡በልብናና፡በንጉሥዋ፡እንዳደረገው፡
እንዲሁ፡በዳቤርና፡በንጉሥዋ፡አደረገ ።

፵ እንዲሁም፡ኢያሱ፡ምድሪቱን፡ሁሉ፡ተራ
ራማውን፡አገር፡ደቡቡንም፡ቈላውንም፡
ቍልቍለቱንም፡ነገሥታቶቻቸውንም፡ሁሉ፡
መታ ፤ ማንንም፡አላስቀረም ፤ የእስራኤል፡
አምላክ፡እግዚአብሔር፡እንዳዘዘውም፡ነፍስ፡
፵፩ ያለበትን፡ሁሉ፡ፈጽሞ፡አጠፋ ። ኢያሱም፡
ከቃዴስ፡በርኔ፡እስከ፡ጋዛ፡ድረስ፡የጎሶም
ንም፡ምድር፡ሁሉ፡እስከ፡ገባዖን፡ድረስ፡
፵፪ መታ ። የእስራኤልም፡አምላክ፡እግዚአብ
ሔር፡ለእስራኤል፡ስለ፡ተዋጋላቸው፡ኢያሱ፡
እነዚህን፡ነገሥታት፡ሁሉ፡ምድራቸውንም፡
፵፫ በአንድ፡ጊዜ፡ያዘ ። ኢያሱም፡ከእርሱም፡
ጋር፡እስራኤል፡ሁሉ፡ወደ፡ሰፈሩ፡ወደ፡
ጌልገላ፡ተመለሱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ እንዲህም፡ሆነ ፤ የአሶር፡ንጉሥ፡ኢያቢስ፡
ይህን፡በሰማ፡ጊዜ፡ወደ፡ማዶን፡ንጉሥ፡ወደ፡
ዮባብ፥ወደ፡ሺምሮንም፡ንጉሥ፥ወደ፡አዚ
፪ ፍም፡ንጉሥ፥በሰሜንም፡በተራራማው፡አገር፥
በኪኔሬትም፡ደቡብ፡በዓረባ፥በቈላውም፥በም
ዕራብም፡በኩል፡ባለ፡በዶር፡ኮረብታ፡ወደ፡
፫ ነበሩ፡ነገሥታት፥በምሥራቅና፡በምዕራብም፡
ወዳለው፡ወደ፡ከነዓናዊው፥ወደ፡አሞራዊ
ውም፥ወደ፡ኬጢያዊውም፥ወደ፡ፌርዛዊ
ውም፥በተራራማውም፡አገር፡ወዳለው፡ወደ፡
ኢያቡሳዊው፥ከአርሞንዔምም፡በታች፡በም
፬ ጽጳ፡ወዳለው፡ወደ፡ኤዊያዊው፡ላከ ። እነዚ
ህም፡ከሠራዊቶቻቸው፡ሁሉ፡ከእጅግም፡ብዙ፡
ፈረሰኞችና፡ሰረገሎች፡ጋር፡ወጡ ፤ በባሕር፡
ዳርም፡እንዳለ፡አሸዋ፡ብዙ፡ሕዝብ፡ነበረ ።
፭ እነዚህም፡ነገሥታት፡ሁሉ፡ተሰብስበው፡
እስራኤልን፡ለመውጋት፡መጥተው፡በማሮን፡
ውኃ፡አጠገብ፡አንድ፡ሆነው፡ሰፈሩ ።

፮ እግዚአብሔርም፡ኢያሱን፡— ነገ፡በዚህ፡
ጊዜ፡ሁሉን፡እንደ፡ሞቱ፡አድርጌ፡በእስራ
ኤል፡እጅ፡አሳልፌ፡እሰጣቸዋለሁና፡አትፍ
ራቸው ፤ የፈረሶቻቸውንም፡ቋንጃ፡ትቈርጣ
ለህ፥ሰረገሎቻቸውንም፡በእሳት፡ታቃጥላ
፯ ለህ፡አለው ። ኢያሱም፡ከሰልፈኞቹ፡ሁሉ፡
ጋር፡በድንገት፡ወደ፡ማሮን፡ውኃ፡መጣባ
፰ ቸው፥ወደቀባቸውም ። እግዚአብሔርም፡
በእስራኤል፡እጅ፡አሳልፎ፡ሰጣቸው ፤ መቱ
አቸውም፥ወደ፡ታላቂቱም፡ሲዶና፥ወደ፡
ማሴሮንም፥በምሥራቅም፡በኩል፡ወዳለው፡

ወደ፡ ምጽጳ፡ ሸለቆ፡ አሳደዱአቸው ፤ ማንንም፡
፱ ሳያስቀሩ፡ መቱአቸው ። ኢያሱም፡ እግዚአብ
ሔር፡ እንዳዘዘው፡ አደረገባቸው ፤ የፈረሶቻቸ
ውንም፡ ቋንጃ፡ ቈረጠ ፥ ሰረገሎቻቸውንም፡
በእሳት፡ አቃጠለ ።

፲ በዚያን፡ ጊዜም፡ ኢያሱ፡ ተመልሶ፡ አሶርን፡
ያዘ ፥ ንጉሥዋንም፡ በሰይፍ፡ ገደለ ፤ አሶርም፡ አስ
ቀድሞ፡ የእነዚህ፡ መንግሥታት፡ ዋና፡ ከተማ፡
፲፩ ነበረች ። በእርስዋም፡ ያሉትን፡ ነፍሳት፡ ሁሉ፡
በሰይፍ፡ ስለት፡ ገደሉ ፥ ፈጽመውም፡ አጠፉ
አቸው ፤ እስትንፋስ፡ ያለውንም፡ አላስቀሩም ፤
፲፪ አሶርንም፡ በእሳት፡ አቃጠላት ። የእግዚአብ
ሔርም፡ ባሪያ፡ ሙሴ፡ እንዳዘዘው ፥ ኢያሱ፡
የእነዚህን፡ ነገሥታት፡ ከተሞች፡ ሁሉ ፥ ነገ
ሥታቶቻቸውንም፡ ሁሉ፡ ያዘ ፥ በሰይፍም፡
ስለት፡ መታቸው ፥ ፈጽሞም፡ አጠፋቸው ።
፲፫ እስራኤልም፡ በኮረብቶቹ፡ ላይ፡ የነበሩትን፡
ከተሞች፡ ሁሉ፡ አላቃጠሉም ፤ ነገር፡ ግን፡
፲፬ እስራኤል፡ አሶርን፡ ብቻ፡ አቃጠሉአት ። የእ
ስራኤልም፡ ልጆች፡ የእነዚህን፡ ከተሞች፡
ምርኮ፡ ሁሉ፡ ከብቶቹንም፡ ለራሳቸው፡ ዘረፉ ፤
ሰዎቹን፡ ሁሉ፡ ግን፡ እስኪጠፉ፡ ድረስ፡ በሰ
ይፍ፡ ስለት፡ መቱአቸው ፥ እስትንፋስ፡ ያለው
፲፭ ንም፡ ሁሉ፡ አላስቀሩም ። እግዚአብሔርም፡
ባሪያውን፡ ሙሴን፡ እንዳዘዘው፡ እንዲሁ፡ ሙሴ፡
ኢያሱን፡ አዝዞት፡ ነበር ፥ ኢያሱም፡ እንዲሁ፡
አደረገ ፤ እግዚአብሔር፡ ሙሴን፡ ካዘዘው፡ ሁሉ፡
ምንም፡ አላስቀረም ።

፲፮ ኢያሱም፡ ያን፡ ምድር፡ ሁሉ ፥ ተራራማ
ውን ፥ ደቡቡንም፡ ሁሉ ፥ የጎሶምንም፡ ምድር፡
ሁሉ ፥ ቈላውንም ፥ ዓረባንም ፥ የእስራኤል
፲፯ ንም፡ ተራራማውንና፡ ቈላውን፡ ያዘ ፥ እስከ፡
ሴይርም፡ ከሚያወጣው፡ ወና፡ ከሆነው፡ ተራራ፡
ጀምሮ፡ ከአርሞንዔም፡ ተራራ፡ በታች፡ በሊ
ባኖስም፡ ሸለቆ፡ ውስጥ፡ እስካለው፡ እስከ፡
በኣልጋድ፡ ድረስ ፤ ነገሥታቶቻቸውንም፡
፲፰ ሁሉ፡ ይዞ፡ መታቸው ፥ ገደላቸውም ። ኢያ
ሱም፡ ብዙ፡ ዘመን፡ ከእነዚህ፡ ነገሥታት፡ ሁሉ፡
፲፱ ጋር፡ ይዋጋ፡ ነበር ። በገባዖን፡ ከሚኖሩ፡ ከኤ
ዊያውያን፡ በቀር፡ ከእስራኤል፡ ልጆች፡ ጋር፡
ዕርቅ፡ ያደረገች፡ አንዲት፡ ከተማ፡ አልነበረ
፳ ችም ፤ ሁሉን፡ በሰልፍ፡ ያዙ ። እግዚአብሔር፡
ሙሴን፡ እንዳዘዘ ፥ ያጠፉአቸው፡ ዘንድ፡ ሞገ
ስንም፡ እንዳያገኙ፡ ፈጽመውም፡ እንዲያጠፉ
አቸው ፥ ከእስራኤል፡ ጋር፡ ይጋጠሙ፡ ዘንድ፡
ልባቸውን፡ እንዲያደነድኑ፡ ከእግዚአብሔር፡
ዘንድ፡ ሆነ ።

፳፩ በዚያን፡ ጊዜም፡ ኢያሱ፡ መጣ ፥ ከተራራ
ማውም፡ አገር፡ ከኬብሮንም፡ ከዳቤርም፡ ከአ
ናብም፡ ከእስራኤልም፡ ተራራማ፡ ሁሉ፡ ከይ
ሁዳም፡ ተራራማ፡ ሁሉ፡ የዔናቅን፡ ልጆች፡
ገደለ ፤ ኢያሱም፡ ከከተሞቻቸው፡ ጋር፡ ፈጽሞ፡
፳፪ አጠፋቸው ። በጋዛ፡ በጌትም፡ በአዛጦንም፡
ጥቂቶች፡ ቀሩ፡ እንጂ፡ በእስራኤል፡ ልጆች፡
ምድር፡ ከዔናቅ፡ ልጆች፡ ማንም፡ አልቀረም ።
፳፫ እግዚአብሔርም፡ ለሙሴ፡ እንደ፡ ነገረው፡ ሁሉ፡
ኢያሱ፡ ምድሪቱን፡ ሁሉ፡ ያዘ ፤ ኢያሱም፡ ለእ
ስራኤል፡ እንደ፡ ክፍላቸውና፡ እንደ፡ ነገዳቸው፡
ርስት፡ አድርጎ፡ ምድሪቱን፡ ሰጣቸው ፤ ምድ
ሪቱም፡ ከሰልፍ፡ ዐረፈች ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ የእስራኤልም፡ ልጆች፡ የመቱአቸው ፥ ከአ
ርኖንም፡ ሸለቆ፡ ጀምሮ፡ እስከ፡ አርሞንዔም፡
ተራራ፡ ድረስ፡ በምሥራቅ፡ ያለውን፡ ዓረባ፡
ሁሉ፡ በዮርዳኖስም፡ ማዶ፡ በፀሐይ፡ መውጫ፡
ያለውን፡ አገራቸውን፡ የወረሱአቸው፡ ነገሥ
፪ ታት፡ እነዚህ፡ ናቸው ፤ በሐሴቦን፡ የተቀመ
ጠው ፥ በአርኖንም፡ ሸለቆ፡ አጠገብ፡ ካለችው፡
ከአሮዔር ፥ ከሸለቆውም፡ መካከል፡ ጀምሮ፡ የገ
ለዓድን፡ እኩሌታ፡ እስከ፡ ያቦቅ፡ ወንዝ፡ እስከ፡
፫ አሞን፡ ልጆች፡ ዳርቻ፡ ድረስ ፥ በምሥራቅም፡
በኩል፡ ያለውን፡ ዓረባ፡ እስከ፡ ከኔሬት፡ ባሕር፡
ድረስ ፥ በቤትየሺሞት፡ መንገድ፡ አጠገብ፡ እስካ
ለው፡ እስከ፡ ዓረባ፡ ባሕር፡ እስከ፡ ጨው፡ ባሕር፡
ድረስ ፥ በደቡብም፡ በኩል፡ ከፈስጋ፡ ተራራ፡
አፋፍ፡ በታች፡ ያለውን፡ ምድር፡ የገዛው፡
፬ የአሞራውያን፡ ንጉሥ፡ ሴዎን ፤ ከራፋይምም፡
ወገን፡ የቀረ ፥ በአስታሮትና፡ በኤድራይ፡ የተ
፭ ቀመጠው ፥ የአርሞንዔምንም፡ ተራራ ፥ ሰል
ካን ፥ ባሳንንም፡ ሁሉ፡ እስከ፡ ጌሹራውያንና፡
እስከ፡ ማዕካታውያን፡ ዳርቻ ፥ የገለዓድንም፡
እኩሌታ፡ እስከ፡ ሐሴቦን፡ ንጉሥ፡ እስከ፡
ሴዎን፡ ዳርቻ፡ ድረስ፡ የገዛው፡ የባሳን፡ ንጉሥ፡
፮ ዐግ ። የእግዚአብሔር፡ ባሪያ፡ ሙሴና፡ የእስ
ራኤል፡ ልጆች፡ መቱአቸው ፤ የእግዚአብሔ
ርም፡ ባሪያ፡ ሙሴ፡ ርስት፡ አድርጎ፡ ለሮቤል፡
ልጆች፡ ለጋድም፡ ልጆች፡ ለምናሴም፡ ነገድ፡
እኩሌታ፡ ምድሪቱን፡ ሰጣቸው ።

፯፡፰ በዮርዳኖስም፡ ማዶ፡ በምዕራብ፡ በኩል፡
በሊባኖስ፡ ሸለቆ፡ ካለችው፡ ከበኣልጋድ፡
ወደ፡ ሴይር፡ እስከሚያወጣው፡ ወና፡ እስከ፡
ሆነው፡ ተራራ፡ ድረስ፡ ኢያሱ፡ በየክፍላቸው፡
ርስት፡ አድርጎ፡ ለእስራኤል፡ ነገድ፡ በሰጣት፡
ምድር ፥ በተራራማው፡ አገር ፥ በቈላውም ፥
በዓረባም ፥ በቍልቍለቱም ፥ በምድረ፡ በዳ
ውም ፥ በደቡብም፡ ያሉ፡ ኬጢያውያን፡ አሞ
ራውያንም፡ ከነዓናውያንም፡ ፌርዛውያንም፡
ኤዊያውያንም፡ ኢያቡሳውያንም፡ የሆኑ፡ ኢያ
ሱና፡ የእስራኤል፡ ልጆች፡ የመቱአቸው፡ የም
፱ ድር፡ ነገሥታት፡ እነዚህ፡ ናቸው ፤ የኢያሪኮ፡
ንጉሥ ፥ በቤቴል፡ አጠገብ፡ ያለችው፡ የጋይ፡
፲ ንጉሥ ፥ የኢየሩሳሌም፡ ንጉሥ ፥ የኬብሮን፡
፲፩ ንጉሥ ፥ የየርሙት፡ ንጉሥ ፥ የለኪሶ፡ ንጉሥ ፥
፲፪፡፲፫ የኤግሎም፡ ንጉሥ ፥ የጌዝር፡ ንጉሥ ፥ የዳቤር፡
፲፬ ንጉሥ ፥ የጌድር፡ ንጉሥ ፥ የሔርማ፡ ንጉሥ ፥
፲፭ የዓራድ፡ ንጉሥ ፥ የልብና፡ ንጉሥ ፥ የዓዶላም፡
፲፮ ንጉሥ ፥ የመቄዳ፡ ንጉሥ ፥ የቤቴል፡ ንጉሥ ፥

፲፯፡፲፰ የታጱዋ ፡ ንጉሥ ÷ የአፌር ፡ ንጉሥ ÷ የአፌቅ ፡
፲፱ ንጉሥ ÷ የለሸሮን ፡ ንጉሥ ÷ የማዶን ፡ ንጉሥ ÷
፳ የአሶር ፡ ንጉሥ ÷ የሺምሮን ፡ ሚሮን ፡ ንጉሥ ÷
፳፩ የአዚፍ ፡ ንጉሥ ÷ የታዕናክ ፡ ንጉሥ ÷ የመ
፳፪ ጊዶ ፡ ንጉሥ ÷ የቃዴስ ፡ ንጉሥ ÷ በቀርሜ
፳፫ ሎስ ፡ የነበረ ፡ የዮቅንዓም ፡ ንጉሥ ÷ በዶር ፡ ክረ
ብታ ፡ የነበረ ፡ የዶር ፡ ንጉሥ ÷ የጌልገላ ፡ አሕ
፳፬ ዛብ ፡ ንጉሥ ÷ የቴርሳ ፡ ንጉሥ ÷ ነገሥታቱ ፡
ሁሉ ፡ ሠላሳ ፡ አንድ ፡ ናቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ ኢያሱም ፡ ሸመገለ ፡ በዕድሜም ፡ አረጀ ፤ እግ
ዚአብሔርም ፡ አለው ፡— አንተ ፡ ሸመገልህ ÷
በዕድሜህም ፡ አረጀህ ፤ ያልተወረሰች ፡ እጅግ ፡
፪ ብዙ ፡ ምድር ፡ ገና ፡ ቀርታለች ፤ የቀረችውም ፡
ምድር ፡ ይህች ፡ ናት ÷ የፍልስጥኤማውያንና ፡
፫ የጌሹራውያን ፡ አገር ፡ ሁሉ ÷ በግብፅ ፡ ፊት ፡
ካለው ፡ ከሺሖር ፡ ወንዝ ፡ ጀምሮ ፡ በሰሜን ፡
በኩል ፡ እስካለችው ፡ የከነዓናውያን ፡ ሆና ፡
እስከ ፡ ተቈጠረችው ፡ እስከ ፡ አቃሮን ፡ ዳርቻ ፡
ድረስ ÷ የጋዛ ÷ የአዛጦን ÷ የአስቀሎና ÷ የጌት ÷
የአቃሮን ÷ አምስቱ ፡ የፍልስጥኤማውያን ፡ መኳ
፬ ንንት ÷ በደቡብም ፡ በኩል ፡ የኤዋውያን ÷ የከነ
ዓናውያንም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ÷ ለሲዶናውያንም ፡
የምትሆን ፡ መዓራ ፡ እስከ ፡ አሞራውያን ፡ ዳርቻ ፡
፭ እስከ ፡ አፌቅ ፡ ድረስ ÷ የጌባላውያውንም ፡
ምድር ÷ በምሥራቅም ፡ በኩል ፡ ከአርሞንዔም ፡
ተራራ ፡ በታች ፡ ካለችው ፡ በአልጋድ ፡ ጀምሮ ፡
እስከ ፡ ሐማት ፡ መግቢያ ፡ ድረስ ፡ ያለችው ፡
፮ ሊባኖስ ፡ ሁሉ ÷ በተራራማውም ፡ አገር ፡ የሚኖ
ሩትን ፡ ሁሉ ፡ ከሊባኖስ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ማሴ
ሮን ፡ ድረስ ፡ ሲዶናውያን ፡ ሁሉ ፤ እነዚህን ፡
ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ አባርራቸዋለሁ ፤
እንዳዘዝሁህም ፡ ምድራቸውን ፡ ለእስራኤል ፡
፯ ርስት ፡ አድርገህ ፡ አካፍላቸው ። አሁንም ፡
ይህን ፡ ምድር ፡ ለዘጠኙ ፡ ነገድ ፡ ለምናሴም ፡
ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ርስት ፡ አድርገህ ፡ ክፈለው ።
፰ የእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ እንደ ፡ ሰጣ
ቸው ፡ ከእርሱ ፡ ከምናሴ ፡ ጋር ፡ የሮቤልና ፡
የጋድ ፡ ልጆች ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ በዮርዳ
ኖስ ፡ ማዶ ፡ ሙሴ ፡ የሰጣቸውን ፡ ርስታቸውን ፡
፱ ተቀበሉ ። በአርኖን ፡ ሸለቆ ፡ ዳር ፡ ካለችው ፡
ከአሮዔር ÷ በሸለቆውም ፡ መካከል ፡ ካለችው ፡
ከተማ ፡ ጀምሮ ፡ የሜድባን ፡ ሜዳ ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡
፲ ዲቦን ፡ ድረስ ÷ በሐሴቦንም ፡ የነገሠ ፡ የአሞራ
ውያን ፡ ንጉሥ ፡ የሴዎን ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡
፲፩ እስከ ፡ አሞን ፡ ልጆች ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ÷ ገለዓ
ድንም ÷ የጌሹራውያንንና ፡ የማዕካታውያንን ፡
ዳርቻ ፡ ሁሉ ÷ የአርሞንዔምንም ፡ ተራራ ፡ ሁሉ ÷
፲፪ ባሳንንም ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ሰልካ ፡ ድረስ ÷ በባ
ሳን ፡ የነበረውን ፡ በአስታሮትና ፡ በኤድራይ ፡
የነገሠውን ፡ የዐግን ፡ መንግሥት ፡ ሁሉ ፤ እር
ሱም ፡ ከራፋይም ፡ የቀረ ፡ ነበረ ፤ እነዚህንም ፡
፲፫ ሙሴ ፡ መታቸው ፡ አወጣቸውም ። የእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ ጌሹራውያንንና ፡ ማዕካታ
ውያንን ፡ አላወጡም ፤ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ ጌሹ
ርና ፡ ማዕካት ፡ በእስራኤል ፡ መካከል ፡ ይኖራሉ ።
፲፬ ለሌዊ ፡ ነገድ ፡ ግን ፡ ርስት ፡ አልሰጠም ፤ ለእስ
ራኤል ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የቀረበው ፡
በእሳት ፡ የተደረገ ፡ መሥዋዕት ፡ ርስታቸው ፡
ነው ÷ እርሱ ፡ እንደ ፡ ተናገራቸው ።
፲፭ ሙሴም ፡ ለሮቤል ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ በየወገና
፲፮ ቸው ፡ ርስትን ፡ ሰጣቸው ። ድንበራቸውም ፡
በአርኖን ፡ ሸለቆ ፡ ዳር ፡ ካለችው ፡ ከአሮዔር ፡
ጀምሮ ፡ በሸለቆው ፡ መካከል ፡ ያለችው ፡ ከተማ ÷
፲፯ የሜድባ ፡ ሜዳ ፡ ሁሉ ÷ ሐሴቦንም ÷ በሜዳውም ፡
ያሉት ፡ ከተሞችዋ ፡ ሁሉ ÷ ዲቦን ÷ ባሞትበ
፲፰ አል ÷ ቤትበአልምዖን ÷ ያህጽ ÷ ቅዴሞት ÷
፲፱ ሜፍዓት ÷ ቂርያታይም ÷ ሴባማ ÷ በሸለቆውም ፡
፳ ተራራ ፡ ያለችው ፡ ጼሬትሻሐር ÷ ቤተ ፡ ፌጎር ÷
ከፈስጋ ፡ ተራራ ፡ በታች ፡ ያለው ፡ ምድር ÷
፳፩ ቤትየሺሞት ÷ የሜዳውም ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ÷
በሐሴቦንም ፡ የነገሠው ፡ የአሞራውያን ፡ ንጉሥ ፡
የሴዎን ፡ መንግሥት ፡ ሁሉ ፡ ነበረ ፤ ሙሴም ፡
እርሱንና ፡ በምድሪቱ ፡ የተቀመጡትን ፡ የሴ
ዎንን ፡ መሳፍንት ÷ የምድያምን ፡ አለቆች ፡
ኤዊን ÷ ሮቆምን ÷ ሱርን ÷ ሑርን ÷ ሪባን ፡ መታ
፳፪ ቸው ። ከገደሉአቸውም ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ የእስ
ራኤል ፡ ልጆች ፡ ምዋርተኛውን ፡ የቢዖርን ፡
፳፫ ልጅ ፡ በለዓምን ፡ በሰይፍ ፡ ገደሉት ። የሮቤ
ልም ፡ ልጆች ፡ ድንበር ፡ የዮርዳኖስ ፡ ወንዝና ፡
ዳርቻው ፡ ነበረ ። የሮቤል ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡
ከተሞቻቸውም ፡ መንደሮቻቸውም ፡ በየወገኖ
ቻቸው ፡ ይህ ፡ ነበረ ።
፳፬ ሙሴም ፡ ለጋድ ፡ ነገድ ፡ ለጋድም ፡ ልጆች ፡
በየወገኖቻቸው ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ ሰጣቸው ።
፳፭ ድንበራቸውም ፡ ኢያዜርና ፡ የገለዓድ ፡ ከተ
ሞች ፡ ሁሉ ÷ የአሞንም ፡ ልጆች ፡ ምድር ፡ እኩ
ሌታ ፡ በረባት ፡ ፊት ፡ እስካለችው ፡ እስከ ፡ አሮ
፳፮ ዔር ፡ ድረስ ÷ ከሐሴቦን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ራማት
ምጽጴ ÷ እስከ ፡ ብጦኒም ፡ ድረስ ÷ ከመሃናይም ፡
፳፯ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዳቤር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ÷ በሸለ
ቆውም ፡ ቤትሀራም ÷ ቤትኒምራ ÷ ሱኮት ÷
ጻፎን ÷ የሐሴቦን ፡ ንጉሥ ፡ የሴዎን ፡ መንግ
ሥት ፡ ቅሬታ ፡ ነበረ ። ድንበሩም ፡ ዮርዳኖስና ፡
በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ባለው ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡
የኪኔሬት ፡ ባሕር ፡ ወዲያኛው ፡ ዳርቻ ፡ ነበረ ።
፳፰ የጋድ ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡ ከተሞቻቸውም ፡ መን
ደሮቻቸውም ፡ በየወገኖቻቸው ፡ ይህ ፡ ነበረ ።
፳፱ ሙሴም ፡ ለምናሴ ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ርስት ፡
ሰጣቸው ፤ ለምናሴም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ እኩ
፴ ሌታ ፡ በየወገኖቻቸው ፡ ይህ ፡ ነበረ ። ድንበራቸ
ውም ፡ ከመሃናይም ፡ ጀምሮ ፡ የባሳን ፡ ንጉሥ ፡
የዐግ ፡ መንግሥት ÷ ባሳን ፡ ሁሉ ÷ በባሳንም ፡
ያሉት ፡ የኢያዕር ፡ መንደሮች ፡ ሁሉ ፡ ስድሳው ፡
፴፩ ከተሞች ÷ የገለዓድም ፡ እኩሌታ ÷ በባሳንም ፡
ያሉት ፡ የዐግ ፡ መንግሥት ፡ ከተሞች ÷ አስታ
ሮትና ፡ ኤድራይ ፡ ነበረ ። እነዚህም ፡ ለምናሴ ፡

ልጅ፡ለማኪር፡ልጆች፡ሆኑ ፤ ለማኪር፡ልጆች፡
እኩሌታ ፡ በየወገኖቻቸው ፡ ይህ ፡ ነበረ ።
፴፪ ሙሴ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ በኢያሪኮ ፡ አን
ጻር ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በሞዓብ ፡ ሜዳ ፡ ሳለ ፡
፴፫ የከፈለው ፡ ርስት ፡ ይህ ፡ ነው ። ለሌዊ ፡ ነገድ ፡
ግን ፡ ሙሴ ፡ ርስት ፡ አልሰጠም ፤ የእስራኤል ፡
አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳላቸው ፡ ርስታ
ቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡
የወረሱት ፥ ካህኑ ፡ አልዓዛርና ፡ የነዌ ፡ ልጅ ፡
ኢያሱ፡የእስራኤልም፡ልጆች፡ነገድ፡የአባቶቻ
ቸው ፡ አለቆች ፡ ያካፈሉአቸው ፡ ርስት ፡ ይህ ፡
፪ ነው ፤ እግዚአብሔር ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ እንዳዘዘ፡
ለዘጠኙ፡ነገድና፡ለእኩሌታው፡በየርስታቸው፡
፫ በዕጣ ፡ አካፈሉአቸው ። ለሁለቱ፡ነገድና ፡ ለእ
ኩሌታው ፡ ነገድ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ሙሴ ፡
ርስት ፡ ሰጥቶ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በመካከላ
ቸው ፡ ለሌዋውያን ፡ ርስት ፡ አልሰጣቸውም ።
፬ የዮሴፍ ፡ ልጆች ፡ ምናሴና ፡ ኤፍሬም ፡ ሁለት ፡
ነገዶች ፡ ነበሩ ፤ ለሌዋውያንም ፡ ከሚቀመጡብ
ቸው ፡ ከተሞች ፡ ለእንስሶቻቸውና ፡ ለከብቶቻ
ቸውም ፡ ከሚሆን ፡ መሰምርያቸው ፡ በቀር ፡
በምድሩ ፡ ውስጥ ፡ ድርሻ፡አልሰጡአቸውም ።
፭ እግዚአብሔር ፡ ሙሴን ፡ እንዳዘዘ ፡ እንዲሁ ፡
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ አደረጉ ፥ ምድሪቱንም ፡
ተካፈሉ ።
፮ የይሁዳም ፡ ልጆች ፡ በጌልገላ ፡ ወደ ፡ ኢያሱ ፡
ቀረቡ ፤ ቄኔዛዊውም ፡ የዮፎኒ ፡ ልጅ ፡ ካሌብ ፡
አለው ፡— ለአምላክ ፡ ሰው ፡ ለሙሴ ፡ ስለ ፡ እኔና ፡
ስለ ፡ አንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ በቃዴስ ፡ በርኔ ፡
፯ የተናገረውን ፡ ነገር ፡ ታውቃለህ ። የእግዚአብ
ሔር ፡ ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ ምድርን ፡ እሰልል ፡ ዘንድ ፡
ከቃዴስ ፡ በርኔ ፡ በላከኝ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ የአርባ ፡
ዓመት ፡ ሰው ፡ ነበርሁ ፤ እኔም ፡ በልቤ ፡ የነበረ
፰ ውን ፡ ቃል ፡ መለስሁለት ። ከእኔ ፡ ጋር ፡ የወጡ ፡
ወንድሞቼ ፡ ግን ፡ የሕዝቡን ፡ ልብ ፡ አቀለጡ ፤
እኔ ፡ ግን ፡ አምላኬን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈጽሜ ፡
፱ ተከተልሁ ። ሙሴም ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡— አምላ
ኬን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈጽመህ ፡ ተከትለሃ
ልና ፡ እግርህ ፡ የረገጠው ፡ ምድር ፡ ለአንተና ፡
ለልጆችህ ፡ ለዘላለም ፡ በእርግጥ ፡ ርስት ፡ ይሆ
፲ ናል ፡ ብሎ ፡ ማለ ። አሁንም ፥ እነሆ ፥ እግዚአ
ብሔር ፡ ለሙሴ ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፥
እስራኤል ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ሲዞሩ ፥ እርሱ ፡
እንደ ፡ ተናገረኝ ፡ እግዚአብሔር ፡ እነዚህን ፡
አርባ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ በሕይወት ፡ አኖረኝ ፤
አሁንም ፥ እነሆ ፥ ለእኔ ፡ ዛሬ ፡ ሰማንያ ፡ አም
፲፩ ስት ፡ ዓመት ፡ ሆነኝ ። ሙሴም ፡ በላከኝ ፡ ጊዜ ፡
እንደ ፡ ነበርሁ ፥ ዛሬ ፡ ጕልበታም ፡ ነኝ ፤ ጕል
በቴም ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፥ እንዲሁ ፡
ዛሬ ፡ ለመዋጋት ፡ ለመውጣትም ፡ ለመግባትም ፡
፲፪ ጕልበቴ ፡ ያው ፡ ነው ። አሁን ፡ እንግዲህ ፡ በዚ
ያን ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ የተናገረውን ፡ ይህን ፡
ተራራማ ፡ አገር ፡ስጠኝ ፤ አንተ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡
ዔናቃውያን ፡ ታላላቆችና ፡ የተመሸጉ ፡ ከተሞ
ችም ፡ በዚያ ፡ እንዳሉ ፡ ሰምተህ ፡ ነበር ፤ ምና
ልባት ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ይሆናል ፥
እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተናገረኝ ፡ አሳድዳቸ
ዋለሁ ።
፲፫ ኢያሱም ፡ ባረከው ፤ ለዮፎኒም ፡ ልጅ ፡ ለካ
ሌብ ፡ ኬብሮንን ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ ሰጠው ።
፲፬ ስለዚህም ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ ፈጽሞ ፡ ስለ ፡ ተከተለ ፡ ኬብሮን ፡ እስከ ፡
ዛሬ ፡ ለቄኔዛዊው ፡ ለዮፎኒ ፡ ልጅ ፡ ለካሌብ ፡
፲፭ ርስት ፡ ሆነች ። የኬብሮንም ፡ ስም ፡ አስቀድሞ ፡
ቂርያትአርባቅ ፡ ትባል ፡ ነበር ፤ ይህም ፡ አርባቅ ፡
በዔናቅ ፡ ሰዎች ፡ መካከል ፡ ከሁሉ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡
ነበረ ። ምድሪቱም ፡ ከውጊያ ፡ ዐረፈች ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ ለይሁዳም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ በየወገናቸው ፡
እስከ ፡ ጺን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ እስከ ፡ ደቡብ ፡ መጨ
ረሻ ፡ እስከ ፡ ኤዶምያስ ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ዕጣ ፡
፪ ሆነላቸው ። በደቡብም ፡ በኩል ፡ ያለው ፡ ድን
በራቸው ፡ እስከ ፡ ጨው ፡ ባሕር ፡ መጨረሻ ፡
ወደ ፡ ደቡብ ፡ እስከሚያይ ፡ እስከ ፡ ባሕር ፡ ልሳን ፡
፫ ነበረ ። ከዚያም ፡ በአቅረቢም ፡ ዐቀበት ፡ በደ
ቡብ ፡ በኩል ፡ ወጣ ፥ ወደ ፡ ጺንም ፡ አለፈ ፥
በቃዴስ ፡ በርኔ ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ በኩል ፡ ወጣ ፥
በሐጽሮንም ፡ በኩል ፡ አለፈ ፥ ወደ ፡ አዳርም ፡
፬ ወጣ ፥ ወደ ፡ ቀርቃ ፡ ዞረ ፥ ወደ ፡ አጽሞንም ፡
አለፈ ፥ በግብፅም ፡ ወንዝ ፡ በኩል ፡ ወጣ ፥ የድ
ንበሩም ፡ መውጫ ፡ በባሕሩ ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ፤
በደቡብ ፡ በኩል ፡ ያለው ፡ ድንበራቸው ፡ ይህ ፡
፭ ነው ። በምሥራቅም ፡ በኩል ፡ ያለው ፡ ድን
በር ፡ እስከ ፡ ጨው ፡ ባሕር ፡ እስከ ፡ ዮርዳኖስም ፡
መጨረሻ ፡ ነበረ ። በሰሜንም ፡ በኩል ፡ ያለው ፡
ድንበር ፡ በዮርዳኖስ ፡ መጨረሻ ፡ እስካለው ፡
፮ እስከ ፡ ባሕሩ ፡ ልሳን ፡ ድረስ ፡ ነበረ ፤ ከዚያም ፡
ድንበሩ ፡ ወደ ፡ ቤትሖግላ ፡ ወጣ ፥ በቤትዓረባ ፡
በሰሜን ፡ በኩል ፡ አለፈ ፥ ወደ ፡ ሮቤልም ፡
፯ ልጅ ፡ ወደ ፡ በሀን ፡ ድንጋይ ፡ ወጣ ፤ ድንበሩም ፡
ከአኮር ፡ ሸለቆ ፡ ወደ ፡ ዳቤር ፡ ወጣ ፥ በሰሜን ፡
በኩል ፡ በአዱሚም ፡ ዐቀበት ፡ ፊት ፡ ለፊት ፥
በወንዙም ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ወዳለችው ፡ ወደ ፡
ጌልገላ ፡ ተመለከተ ፤ ድንበሩም ፡ ወደ ፡ ቤት
ሳሚስ ፡ ውኃ ፡ አለፈ ፥ መውጫውም ፡ በዓይን
፰ ሮጌል ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ፤ ድንበሩም ፡ በሄኖም ፡
ልጅ ፡ ሸለቆ ፡ አጠገብ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወደምት
ባለው ፡ ወደ ፡ ኢያቡሳዊው ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡
ወገን ፡ ወጣ ፤ ድንበሩም ፡ በራፋይም ፡ ሸለቆ ፡
ዳር ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ባለው ፡ በሄኖም ፡ ሸለቆ ፡
ፊት ፡ ለፊት ፡ በምዕራብ ፡ ወገን ፡ ወዳለው ፡
፱ ተራራ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ወጣ ፤ ድንበሩም ፡ ከተራ
ራው ፡ ራስ ፡ ወደ ፡ ኔፍቶ ፡ ውኃ ፡ ምንጭ ፡ ደረስ ፥
ወደ ፡ ዔፍሮንም ፡ ተራራ ፡ ከተሞች ፡ ወጣ ፤

ቂርያትይዓሪም ፡ ወደምትባል ፡ ወደ ፡ በኣላ ፡
፲ ደረሰ ፡፡ ድንበሩም ፡ ከበኣላ ፡ በምዕራብ ፡ በኩል ፡
ወደ ፡ ሴይር ፡ ተራራ ፡ ዞረ ፤ ከሳሎን ፡ ወደም
ትባል ፡ ወደ ፡ ይዓሪም ፡ ተራራ ፡ ወገን ፡ በሰሜን ፡
በኩል ፡ አለፈ ፤ ወደ ፡ ቤትሳሚስ ፡ ወረደ ፥ በተ
፲፩ ምና ፡ በኩልም ፡ አለፈ ፡፡ ድንበሩም ፡ ወደ ፡
አቃሮን ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ወገን ፡ ወጣ ፤ ወደ ፡
ሽክሮን ፡ ደረሰ ፤ ወደ ፡ በኣላ ፡ ተራራ ፡ አለፈ ፥
በየብኒኤል ፡ በኩልም ፡ ወጣ ፤ የድንበሩም ፡
፲፪ መውጫ ፡ በባሕሩ ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ፡፡ በምዕራ
ቡም ፡ በኩል ፡ ያለው ፡ ድንበር ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡
ባሕርና ፡ እስከ ፡ ዳርቻው ፡ ድረስ ፡ ነበረ ፡፡ ለይ
ሁዳ ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፡ በዙሪያው ፡ ያሉ ፡
ድንበራቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፡፡

፲፫ እግዚአብሔርም ፡ ኢያሱን ፡ እንዳዘዘው ፡ ለዮ
ፎኒ ፡ ልጅ ፡ ለካሌብ ፡ በይሁዳ ፡ ልጆች ፡ መካ
ከል ፡ ቂርያትአርባቅ ፡ የምትባለውን ፡ ከተማ ፡
ድርሻ ፡ አድርጎ ፡ ሰጠው ፤ እርስዋም ፡ ኬብሮን ፡
ናት ፥ ይህም ፡ አርባቅ ፡ የዔናቅ ፡ አባት ፡ ነበረ ፡፡
፲፬ ካሌብም ፡ ሦስቱን ፡ የዔናቅን ፡ ልጆች ፡ ሴሲ
ንና ፡ አኪመንን ፡ ተላሚንም ፡ ከዚያ ፡ አሳደደ ፡፡
፲፭ ከዚያም ፡ በዳቤር ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ወጣ ፤ የዳ
ቤርም ፡ ስም ፡ አስቀድሞ ፡ ቂርያትሤፍር ፡
፲፮ ትባል ፡ ነበር ፡፡ ካሌብም ፡— ቂርያትሤፍርን ፡
ለሚመታ ፡ ለሚይዛትም ፡ ልጄን ፡ ዓክሳን ፡
፲፯ አጋባዋለሁ ፡ አለ ፡፡ የካሌብ ፡ ወንድም ፡ የቄ
ኔዝ ፡ ልጅ ፡ ጎቶንያል ፡ ያዛት ፤ ልጁንም ፡ ዓክ
፲፰ ሳን ፡ አጋባው ፡፡ እርስዋም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ በመ
ጣች ፡ ጊዜ ፡ ከአባትዋ ፡ እርሻ ፡ እንዲለምን ፡
መከረችው ፤ እርስዋም ፡ ከአህያዋ ፡ ወረደች ፤
፲፱ ካሌብም ፡— ምን ፡ ፈለግሽ ? አላት ፡፡ እርስ
ዋም ፡— በረከትን ፡ ስጠኝ ፤ በደቡብ ፡ በኩል ፡
ያለውን ፡ ምድር ፡ ሰጥተኸኛልና ፡ አሁን ፡ ደግሞ ፡
የውኃውን ፡ ምንጭ ፡ ስጠኝ ፡ አለችው ፡፡ እር
ሱም ፡ የላይኛውንና ፡ የታችኛውን ፡ ምንጭ ፡
ሰጣት ፡፡

፳ በየወገኖቻቸውም ፡ የይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡
ርስት ፡ ይህ ፡ ነው ፡፡

፳፩ በደቡብም ፡ በኩል ፡ በምድራቸው ፡ ዳርቻ ፡
አጠገብ ፡ እስከ ፡ ኤዶምያስ ፡ ድንበር ፡ ያሉት ፡
የይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ከተሞች ፡ እነዚህ ፡
፳፪ ነበሩ ፤ ቀብስኤል ፥ ዔዴር ፥ ያጉር ፥ ቂና ፥
፳፫ ዲሞና ፥ ዓድዓዳ ፥ ቃዴስ ፥ ሐጾር ፥ ዪት
፳፬፡፳፭ ናን ፥ ዚፍ ፥ ጤሌም ፥ በዓሎት ፥ ሐጾርሐ
ዳታ ፥ ሐጾር ፡ የምትባለውም ፡ ቂርያትሐጾር ፥
፳፮፡፳፯ አማም ፥ ሽማዕ ፥ ሞላዳ ፥ ሐጾርጋዳ ፥ ሐሽሞን ፥
፳፰ ቤትጳሌጥ ፥ ሐጾርሹዓል ፥ ቤርሳቤህ ፥ ቢዝ
፳፱፡፴ ዮትያ ፥ በኣላ ፥ ዒዪም ፥ ዓጼም ፥ ኤልቶላድ ፥
፴፩ ኪሲል ፥ ሔርማ ፥ ጺቅላግ ፥ ማድማና ፥ ሳን
፴፪ ሳና ፥ ልባዎት ፥ ሺልሂም ፥ ዓይን ፥ ሪሞን ፤ ሀያ ፡
ዘጠኝ ፡ ከተሞችና ፡ መንደሮቻቸው ፡፡

፴፫፡፴፬ በቈላው ፡ ኤሽታኦል ፥ ጾርዓ ፥ አሽና ፥ ዛኖዋ ፥
፴፭ ዓይንገኒም ፥ ታጱዋ ፥ ዓይናም ፥ የርሙት ፥
፴፮ ዓዶላም ፥ ሰኰት ፥ ዓዜቃ ፥ ሽዓራይም ፥ ዓዲ
ታይም ፥ ግዴራ ፥ ግዴሮታይም ፤ አሥራ ፡
አራት ፡ ከተሞችና ፡ መንደሮቻቸው ፡፡

፴፯፡፴፰ ጽናን ፥ ሐዳሽ ፥ ሚግዳልጋድ ፥ ዲልዓን ፥
፴፱ ምጽጳ ፥ ዮቅትኤል ፥ ለኪሶ ፥ በጽቃት ፥
፵፡፵፩ አዶላም ፥ ከበን ፥ ለሕማስ ፥ ኪትሊሽ ፥ ግዴ
ሮት ፥ ቤትዳጎን ፥ ናዕማ ፥ መቄዳ ፤ አሥራ ፡
ስድስት ፡ ከተሞችና ፡ መንደሮቻቸው ፡፡

፵፪፡፵፫ ልብና ፥ ዔቴር ፥ ዓሻን ፥ ይፍታሕ ፥ አሽና ፥
፵፬ ንጺብ ፥ ቅዒላ ፥ አክዚብ ፥ መሪሳ ፤ ዘጠኝ ፡
ከተሞችና ፡ መንደሮቻቸው ፡፡

፵፭ አቃሮን ፡ ከተመሸጉና ፡ ካልተመሸጉ ፡ መን
፵፮ ደሮችዋ ፡ ጋር ፤ ከአቃሮንም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ባሕር ፡ ድረስ ፡ በአዛጦን ፡ አጠገብ ፡ ያሉት ፡
ሁሉ ፡ ከመንደሮቻቸው ፡ ጋር ፡፡

፵፯ አዛጦንና ፡ የተመሸጉና ፡ ያልተመሸጉ ፡
መንደሮችዋም ፥ ጋዛና ፡ የተመሸጉ ፡ ያልተመ
ሸጉም ፡ መንደሮችዋ ፥ እስከ ፡ ግብፅ ፡ ወን
ዝና ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ባሕር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡፡

፵፰ በተራራማውም ፡ አገር ፡ ሳምር ፥ የቲር ፥
፵፱ ሶኮ ፥ ደና ፥ ዳቤር ፡ የምትባለው ፡ ቂርያትሰና ፥
፶፡፶፩ ዓናብ ፥ ኤሽትሞዓ ፥ ዓኒም ፥ ጎሶም ፥ ሖሎን ፥
ጊሎ ፤ አሥራ ፡ አንድ ፡ ከተሞችና ፡ መንደሮ
ቻቸው ፡፡

፶፪፡፶፫ አራብ ፥ ዱማ ፥ ኤሽዓን ፥ ያኒም ፥ ቤትታ
፶፬ ጱዋ ፥ አፌቃ ፥ ሑምጣ ፥ ኬብሮን ፡ የምት
ባል ፡ ቂርያትአርባቅ ፥ ጺዖር ፤ ዘጠኝ ፡ ከተሞ
ችና ፡ መንደሮቻቸው ፡፡

፶፭፡፶፮ ማዖን ፥ ቀርሜሎስ ፥ ዚፍ ፥ ዩጣ ፥ ኢይ
፶፯ ዝራኤል ፥ ዮቅድዓም ፥ ዛኖዋሕ ፥ ቃይን ፥
ጊብዓ ፥ ተምና ፤ አሥር ፡ ከተሞችና ፡ መንደ
ሮቻቸው ፡፡

፶፰፡፶፱ ሐልሑል ፥ ቤትጹር ፥ ጌዶር ፥ ማዕራት ፥
ቤትዓኖት ፥ ኤልትቆን ፤ ስድስት ፡ ከተሞችና ፡
መንደሮቻቸው ፡፡

፷ ቂርያትይዓሪም ፡ የምትባለው ፡ ቂርያትበኣል ፥
ረባት ፤ ሁለት ፡ ከተሞችና ፡ መንደሮቻቸው ፡፡

፷፩ በምድረ ፡ በዳ ፡ ቤትዓረባ ፥ ሚዲን ፥ ስካካ ፥
፷፪ ኒብሻን ፥ የጨው ፡ ከተማ ፥ ዓይንጋዲ ፤ ስድ
ስት ፡ ከተሞችና ፡ መንደሮቻቸው ፡፡

፷፫ በኢየሩሳሌም ፡ የተቀመጡትን ፡ ኢያቡሳ
ውያንን ፡ ግን ፡ የይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ሊያሳድዱ
አቸው ፡ አልተቻላቸውም ፤ ኢያቡሳውያንም ፡
እስከ ፡ ዛሬ ፡ በይሁዳ ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ በኢ
የሩሳሌም ፡ ውስጥ ፡ ተቀምጠዋል ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ፡፡

፩ የዮሴፍም ፡ ልጆች ፡ ዕጣ ፡ በኢያሪኮ ፡ አጠ
ገብ ፡ በምሥራቁ ፡ በኩል ፡ ካለው ፡ ከዮርዳኖስ ፡
አንሥቶ ፡ በምድረ ፡ በዳውና ፡ በተራራማው ፡
፪ በኩል ፡ ከኢያሪኮ ፡ ወደ ፡ ቤቴል ፡ ወጣ ፤ ከቤ
ቴል ፡ ወደ ፡ ሎዛ ፡ ወጣ ፥ በአርካውያንም ፡
፫ ዳርቻ ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ አጣሮት ፡ አለፈ ፥ ወደ ፡
ምዕራብም ፡ እስከ ፡ የፍሌጣውያን ፡ ዳርቻ ፡
እስከ ፡ ታችኛው ፡ ቤትሖሮን ፡ ዳርቻ ፡ እስከ ፡

ጌዝር ፡ ድረስ ፡ ወረደ ፥ መውጫውም ፡ በባሕሩ ፡
፬ አጠገብ ፡ ነበረ ። የዮሴፍም ፡ ልጆች ፡ ምናሴና ፡
ኤፍሬም ፡ ርስታቸውን ፡ ወረሱ ።

፭ የኤፍሬምም ፡ ልጆች ፡ ድንበር ፡ በየወገኖቻ
ቸው ፡ እንደዚህ ፡ ነበረ ፤ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡
የርስታቸው ፡ ድንበር ፡ አጣሮትአዳር ፡ እስከ ፡
፮ ላይኛው ፡ ቤትሖሮን ፡ ድረስ ፡ ነበረ ፤ ድንበ
ሩም ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ወደ ፡ ሚክምታት ፡
በሰሜን ፡ በኩል ፡ ወጣ ፤ ድንበሩም ፡ ወደ ፡ ምሥ
ራቅ ፡ ወደ ፡ ተአናትሴሎ ፡ ዞረ ፥ ወደ ፡ ኢያኖክ ፡
፯ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ አለፈ ፥ ከኢያኖክም ፡
ወደ ፡ አጣሮትና ፡ ወደ ፡ ነዓራት ፡ ወረደ ፤ ወደ ፡
ኢያሪኮም ፡ ደረሰ ፥ ወደ ፡ ዮርዳኖስም ፡ ወጣ ።
፰ ድንበሩም ፡ ከታጱዋ ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ እስከ ፡
ቃና ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ፡ አለፈ ፥ መውጫውም ፡
በባሕሩ ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ። የኤፍሬም ፡ ልጆች ፡
ነገድ ፡ ርስት ፡ በየወገኖቻቸው ፡ ይህ ፡ ነበረ ።
፱ ይኸውም ፡ በምናሴ ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡ መካከል ፡
ለኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ ከተለዩ ፡ ከተሞች ፡ ጋር ፥
ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ከመንደሮቻቸው ፡ ጋር ፥ ነው ።
፲ በጌዝርም ፡ የተቀመጡትን ፡ ከነዓናውያንን ፡ አላ
ሳደዱአቸውም ፥ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ ከነዓና
ውያን ፡ በኤፍሬም ፡ መካከል ፡ ተቀምጠዋል ፤
የጉልበት ፡ ግብርም ፡ ያስገብሩአቸው ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ ለምናሴ ፡ ነገድ ፡ ዕጣ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የዮሴፍ ፡
በኵር ፡ እርሱ ፡ ነውና ። የምናሴም ፡ በኵር ፡
የገለዓድ ፡ አባት ፡ ማኪር ፡ ብርቱ ፡ ሰልፈኛ ፡
፪ ስለ ፡ ነበረ ፡ ገለዓድንና ፡ በሳንን ፡ ወረሰ ። ዕጣ
ውም ፡ ለቀሩት ፡ ለምናሴ ፡ ልጆች ፡ በየወገኖቻ
ቸው ፥ ለአቢዔዝር ፡ ልጆች ፥ ለኬሌግ ፡ ልጆች ፥
ለአሥሪኤል ፡ ልጆች ፥ ለሴኬም ፡ ልጆች ፥ ለአ
ፌር ፡ ልጆች ፥ ለሸሚዳ ፡ ልጆች ፡ ሆነ ፤ የዮ
ሴፍ ፡ ልጅ ፡ የምናሴ ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ በየወ
፫ ገኖቻቸው ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። ለምናሴ ፡ ልጅ ፥
ለማኪር ፡ ልጅ ፥ ለገለዓድ ፡ ልጅ ፥ ለኦፌር ፡
ልጅ ፥ ለሰለጰዓድ ፡ ግን ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ እንጂ ፡
ወንዶች ፡ ልጆች ፡ አልነበሩትም ፡ የሴቶች ፡ ልጆ
ቹም ፡ ስም ፡ ማህለህ ፥ ኑዓ ፥ ዔግላ ፥ ሚልካ ፥
፬ ቲርጻ ፡ ነበረ ። እነርሱም ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ወደ ፡
አልዓዛርና ፡ ወደ ፡ ነዌ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢያሱ ፡
ወደ ፡ አለቆችም ፡ ቀርበው ፡— እግዚአብሔር ፡
በወንድሞቻችን ፡ መካከል ፡ ርስት ፡ እንዲሰጠን ፡
ሙሴን ፡ አዘዘ ፡ አሉ ፤ እግዚአብሔርም ፡ እንዳ
ዘዘ ፡ በአባታቸው ፡ ወንድሞች ፡ መካከል ፡ ርስት ፡
፭ ሰጣቸው ። በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ካለው ፡ ከገለ
ዓድና ፡ ከባሳን ፡ አገር ፡ ሌላ ፡ ለምናሴ ፡ አሥር ፡
፮ ዕጣ ፡ ሆነ ፤ የምናሴ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ በወን
ዶች ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ርስት ፡ ተቀብለዋልና ፤
የገለዓድም ፡ ምድር ፡ ለቀሩት ፡ ለምናሴ ፡ ልጆች ፡
ሆኖአልና ።

፯ የምናሴም ፡ ድንበር ፡ ከአሴር ፡ ጀምሮ ፡ በሴ
ኬም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ እስካለው ፡ እስከ ፡ ሚክም
ታት ፡ ድረስ ፡ ነበረ ፤ ድንበሩም ፡ በቀኝ ፡ በኩል ፡
ወደ ፡ ዓይንታጱዋ ፡ ሰዎች ፡ አለፈ ። የታጱዋ ፡
፰ ምድር ፡ ለምናሴ ፡ ነበረ ፤ በምናሴ ፡ ዳርቻ ፡ ያለው ፡
ታጱዋ ፡ ግን ፡ ለኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ ሆነ ። ድን
፱ በሩም ፡ ወደ ፡ ቃና ፡ ወንዝ ፡ ከወንዙ ፡ በደቡብ ፡
ወገን ፡ ወረደ ፤ በምናሴም ፡ ከተሞች ፡ መካከል ፡
የነበሩት ፡ እነዚህ ፡ ከተሞች ፡ ለኤፍሬም ፡ ሆኑ ፤
የምናሴም ፡ ድንበር ፡ በወንዙ ፡ በኩል ፡ በሰ
ሜን ፡ ወገን ፡ ነበረ ፥ መውጫውም ፡ በባሕሩ ፡
አጠገብ ፡ ነበረ ። በደቡብ ፡ በኩል ፡ ያለው ፡
፲ ለኤፍሬም ፡ ነበረ ፥ በሰሜንም ፡ በኩል ፡ ያለው ፡
ለምናሴ ፡ ነበረ ፥ ድንበሩም ፡ ባሕሩ ፡ ነበረ ፤
በሰሜን ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ አሴር ፥ በምሥራቅም ፡
በኩል ፡ ወደ ፡ ይሳኮር ፡ ደረሰ ። በይሳኮርና ፡
፲፩ በአሴር ፡ መካከል ፡ ቤትሳንና ፡ መንደሮችዋ ፥
ይብልዓምና ፡ መንደሮችዋ ፥ ዶርና ፡ የመንደሮ
ችዋ ፡ ሰዎች ፥ ዓይንዶርና ፡ የመንደሮችዋ ፡
ሰዎች ፥ ታዕናክና ፡ የመንደሮችዋ ፡ ሰዎች ፥
መጊዶና ፡ የመንደሮችዋ ፡ ሰዎች ፥ ሦስቱ ፡ ኮረ
ብቶች ፡ ለምናሴ ፡ ነበሩ ። የምናሴ ፡ ልጆች ፡
፲፪ ግን ፡ የእነዚህን ፡ ከተሞች ፡ ሰዎች ፡ ሊያሳድዱአ
ቸው ፡ አልቻሉም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከነዓናውያን ፡
በዚያ ፡ አገር ፡ በመቀመጥ ፡ ጸኑ ። የእስራኤ
፲፫ ልም ፡ ልጆች ፡ በጸኑ ፡ ጊዜ ፡ ከነዓናውያንን ፡
የጉልበት ፡ ግብር ፡ አስገበሩአቸው ፥ ፈጽመ
ውም ፡ አላሳደዱአቸውም ።

፲፬ የዮሴፍ ፡ ልጆች ፡ ኢያሱን ፡— እኔ ፡ ብዙ ፡
ሕዝብ ፡ ስለ ፡ ሆንሁ ፡ እስከ ፡ አሁንም ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ስለ ፡ ባረከኝ ፡ ለምን ፡ አንድ ፡ ክፍል ፡
አንድም ፡ ዕጣ ፡ ብቻ ፡ ርስት ፡ አድርገህ ፡ ሰጠ
ኸኝ ? አሉት ። ኢያሱም ፡— ብዙ ፡ ሕዝብስ ፡
፲፭ ከሆንህ ፡ ተራራማውም ፡ የኤፍሬም ፡ አገር ፡
ጠብቦህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ወደ ፡ ዱር ፡ ወጥተህ ፡
በፌርዛውያንና ፡ በራፋይም ፡ ምድር ፡ ለአ
ንተ ፡ ስፍራ ፡ መንጥር ፡ አላቸው ። የዮሴፍም ፡
፲፮ ልጆች ፡— ተራራማው ፡ አገር ፡ አይበቃንም ፤
በሸለቆውም ፡ ውስጥ ፡ ለሚኖሩት ፥ በቤትሳ
ንና ፡ በመንደሮችዋ ፡ በኢይዝራኤልም ፡ ሸለቆ ፡
ለሚኖሩት ፡ ከነዓናውያን ፡ የብረት ፡ ሰረገሎች ፡
አላቸው ፡ አሉት ። ኢያሱም ፡ የዮሴፍ ፡ ወገን ፡
፲፯ ለሚሆኑ ፡ ለኤፍሬምና ፡ ለምናሴ ፡— አንተ ፡
ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ነህ ፥ ጽኑም ፡ ኃይል ፡ አለህ ፤
አንድ ፡ ዕጣ ፡ ብቻ ፡ አይሆንልህም ፤ ነገር ፡
፲፰ ግን ፡ ተራራማው ፡ አገር ፡ ለአንተ ፡ ይሆናል ፥
ዱር ፡ እንኳ ፡ ቢሆንም ፡ ትመነጥረዋለህ ፥ ለአን
ተም ፡ ይሆናል ፤ ለከነዓናውያንም ፡ የብረት ፡
ሰረገሎች ፡ ቢሆኑላቸው ፡ የበረቱም ፡ ቢሆኑ ፡
ታሳድዳቸዋለህ ፡ አላቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ በሴሎ ፡
ተሰበሰቡ ፥ በዚያም ፡ የመገናኛውን ፡ ድንኳን ፡
ተከሉ ፤ ምድሩም ፡ ጸጥ ፡ ብሎ ፡ ተገዛላቸው ።
፪ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡ ያልተካፈሉ ፡

፫ ሰባት ፡ ነገድ ፡ ቀርተው ፡ ነበር ። ኢያሱም ፡
የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ አላቸው ፡— የአባቶቻ
ችሁ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሰጣችሁን ፡
ምድር ፡ ትወርሱ ፡ ዘንድ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ለመግ
፬ ባት ፡ ቸል ፡ ትላላችሁ ? ከየነገዱ ፡ ሁሉ ፡ ሦስት ፡
ሦስት ፡ ሰዎች ፡ ምረጡ ፥ እኔም ፡ እልካቸዋለሁ ፤
ተነሥተውም ፡ አገሩን ፡ ይዞራሉ ፥ እንደ ፡ ርስ
ታቸውም ፡ መጠን ፡ ይጽፉታል ፤ ወደ ፡ እኔም ፡
፭ ይመለሳሉ ። በሰባትም ፡ ክፍል ፡ ይከፍሉታል ፤
ይሁዳ ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ በዳርቻው ፡ ውስጥ ፡
ይቀመጣል ፤ የዮሴፍ ፡ ወገኖች ፡ በሰሜን ፡
በኩል ፡ በዳርቻው ፡ ውስጥ ፡ ይቀመጣሉ ።
፮ እናንተም ፡ ምድሩን ፡ በሰባት ፡ ክፍል ፡ ጻፉት ፥
የጻፋችሁትንም ፡ ወዲህ ፡ አምጡልኝ ፤ በአ
ምላካችንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በዚህ ፡
፯ ዕጣ ፡ አጣጥላችኋለሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ የእግዚ
አብሔር ፡ ክህነት ፡ ርስታቸው ፡ ነውና ፡ ለሌ
ዋውያን ፡ በመካከላችሁ ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ የላ
ቸውም ፤ ጋድም ፡ ሮቤልም ፡ የምናሴም ፡ ነገድ ፡
እኩሌታ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በምሥራቅ ፡
በኩል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ የሰጣ
ቸውን ፡ ርስታቸውን ፡ ተቀብለዋል ።

፰ ሰዎችም ፡ ተነሥተው ፡ ሄዱ ፤ ኢያሱም ፡
ምድሩን ፡ ሊጽፉ ፡ የሄዱትን ፡— ሂዱ ፥ ምድ
ሩንም ፡ ዞራችሁ ፡ ጻፉት ፥ ወደ ፡ እኔም ፡ ተመ
ለሱ ፤ በዚህም ፡ በሴሎ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ዕጣ ፡ አጣጥላችኋለሁ ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ።
፱ ሰዎቹም ፡ ሄደው ፡ ምድሩን ፡ ዞሩ ፥ እንደ ፡ ከተ
ሞችም ፡ በሰባት ፡ ክፍል ፡ ከፈሉት ፥ በመጽ
ሐፍም ፡ ጻፉት ፤ ኢያሱም ፡ ወደ ፡ ሰፈረበት ፡
፲ ወደ ፡ ሴሎ ፡ ተመለሱ ። ኢያሱም ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ፊት ፡ በሴሎ ፡ ዕጣ ፡ አጣጣላቸው ፤
በዚያም ፡ ኢያሱ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡
ክፍሎቻቸው ፡ ምድሩን ፡ ከፈለ ።

፲፩ የብንያምም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ዕጣ ፡ በየወገ
ኖቻቸው ፡ ወጣ ፤ የዕጣቸውም ፡ ዳርቻ ፡ በይ
ሁዳ ፡ ልጆችና ፡ በዮሴፍ ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡
፲፪ ወጣ ። በሰሜን ፡ በኩል ፡ ድንበራቸው ፡ ከዮ
ርዳኖስ ፡ ጀመረ ፤ ድንበሩም ፡ ወደ ፡ ኢያ
ሪኮ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ወገን ፡ ወጣ ፥ ከዚያም ፡
በተራራማው ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ወጣ ፥
መውጫውም ፡ በቤትአዌን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
፲፫ ነበረ ። ድንበሩም ፡ ከዚያ ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡
ቤቴል ፡ ወደምትባል ፡ ወደ ፡ ሎዛ ፡ አለፈ ፤ ድን
በሩም ፡ በታችኛው ፡ ቤትሖሮን ፡ በደቡብ ፡
በኩል ፡ ባለው ፡ ተራራ ፡ ወደ ፡ አጣሮትአዳር ፡
፲፬ ወረደ ። ድንበሩም ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ሄደ ፥
በቤትሖሮንም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ካለው ፡ ተራራ ፡
ወደ ፡ ደቡብ ፡ ዞረ ፤ መውጫውም ፡ ቂርያትይ
ዓሪም ፡ በምትባል ፡ በይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ከተማ ፡
በቂርያትበኣል ፡ ነበረ ፤ ይህ ፡ የምዕራቡ ፡
፲፭ ዳርቻ ፡ ነበረ ። የደቡብም ፡ ዳርቻ ፡ ከቂርያት
ይዓሪም ፡ መጨረሻ ፡ ነበረ ፤ ድንበሩም ፡ በምዕ
ራብ ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ነፍቶ ፡ ውኃ ፡ ምንጭ ፡
፲፮ ወጣ ። ድንበሩም ፡ በሄኖም ፡ ልጅ ፡ ሸለቆ ፡
ፊት ፡ ለፊት ፡ ወዳለው ፡ ተራራ ፡ መጨረሻ ፡
ወረደ ፥ እርሱም ፡ በራፋይም ፡ ሸለቆ ፡ በሰሜን ፡
በኩል ፡ ነው ፤ ወደ ፡ ሄኖም ፡ ሸለቆ ፡ ወደ ፡ ኢያ
ቡስ ፡ ዳር ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ወረደ ፥ ወደ ፡
፲፯ ዓይንሮጌልም ፡ ወረደ ። ወደ ፡ ሰሜንም ፡ አለፈ ፡
በቤትሳሚስ ፡ ምንጭ ፡ ላይ ፡ ወጣ ፥ በአዱ
ሚም ፡ ዐቀበት ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡
ጌሊሎት ፡ ደረሰ ፤ ወደ ፡ ሮቤልም ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡
፲፰ ቦሀን ፡ ድንጋይ ፡ ወረደ ፤ በሰሜንም ፡ ወገን ፡
ወደ ፡ ዓረባ ፡ አጠገብ ፡ አለፈ ፥ ወደ ፡ ዓረባም ፡
፲፱ ወረደ ፤ ድንበሩም ፡ ወደ ፡ ቤትሖግላ ፡ ወደ ፡
ሰሜን ፡ ወገን ፡ አለፈ ፤ መውጫውም ፡ በዮር
ዳኖስ ፡ መጨረሻ ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ባለው ፡
በጨው ፡ ባሕር ፡ ልሳን ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ፤ ይህ ፡
፳ የደቡቡ ፡ ዳርቻ ፡ ነበረ ። በምሥራቅም ፡ በኩል ፡
ድንበሩ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ነበረ ። ይህ ፡ በዙሪያቸው ፡
ዳርቻ ፡ በየወገኖቻቸው ፡ የብንያም ፡ ልጆች ፡
ርስት ፡ ነበረ ።

፳፩ የብንያምም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ከተሞች ፡ በየ
ወገኖቻቸው ፡ እነዚህ ፡ ነበሩ ፤ ኢያሪኮ ፥ ቤት
፳፪ ሖግላ ፥ ዓመቀጺጽ ፥ ቤትዓረባ ፥ ዘማራይም ፥
፳፫፡፳፬ ቤቴል ፥ ዓዊም ፥ ፋራ ፥ ኤፍራታ ፥ ከፊርዓ
ሞናይ ፥ ዖፍኒ ፥ ጋባ ፤ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ከተ
፳፭ ሞችና ፡ መንደሮቻቸው ። ገባዖን ፥ ራማ ፥
፳፮ ብኤሮት ፥ ምጽጳ ፥ ከፊራ ፥ አሞቂ ፥
፳፯፡፳፰ ሬቄም ፥ ይርጵኤል ፥ ተርአላ ፥ ጼላ ፥ ኤሌፍ ፥
ኢየሩሳሌም ፡ የምትባል ፡ የኢያቡስ ፡ ከተማ ፥
ቂርያትጊብዓት ፤ አሥራ ፡ ሦስት ፡ ከተሞ
ችና ፡ መንደሮቻቸው ። የብንያም ፡ ልጆች ፡
ርስት ፡ በየወገኖቻቸው ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ ሁለተኛውም ፡ ዕጣ ፡ ለስምዖን ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡
በየወገኖቻቸው ፡ ወጣ ፤ ርስታቸውም ፡ በይሁዳ ፡
፪ ልጆች ፡ ርስት ፡ መካከል ፡ ነበረ ። እነዚህም ፡
ርስታቸው ፡ ሆኑላቸው ፤ ቤርሳቤህ ፥ ሤባ ፥
፫፡፬ ሞላዳ ፥ ሐጸርሹዓል ፥ ባላ ፥ ዔጼም ፥ ኤልቶ
፭ ላድ ፥ በቱል ፥ ሔርማ ፥ ጺቅላግ ፥ ቤትማርካ
፮ ቦት ፥ ሐጸርሱሳ ፥ ቤተ ፡ ለባኦት ፥ ሻሩሔን ፤
አሥራ ፡ ሦስት ፡ ከተሞችና ፡ መንደሮቻቸው ፤
፯ ዓይን ፥ ሪሞን ፥ ዔቴር ፥ ዓሻን ፤ አራት ፡ ከተሞ
፰ ችና ፡ መንደሮቻቸው ፤ እስከ ፡ በዕላትብኤርና ፡
እስከ ፡ ደቡቡ ፡ ራማት ፡ ድረስ ፡ በእነዚህ ፡ ከተ
ሞች ፡ ዙሪያ ፡ ያሉ ፡ መንደሮች ፡ ሁሉ ። የስም
ዖን ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ርስት ፡ በየወገኖቻቸው ፡
፱ ይህ ፡ ነበረ ። ከይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ክፍል ፡ የስም
ዖን ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡ ሆነ ፤ የይሁዳም ፡ ልጆች ፡
እድል ፡ ፈንታ ፡ ስለ ፡ በዛባቸው ፡ የስምዖን ፡
ልጆች ፡ በርስታቸው ፡ መካከል ፡ ወረሱ ።

፲ ሦስተኛውም ፡ ዕጣ ፡ ለዛብሎን ፡ ልጆች ፡ በየ
ወገኖቻቸው ፡ ወጣ ፤ የርስታቸውም ፡ ድንበር ፡
፲፩ ወደ ፡ ሣሪድ ፡ ደረሰ ፤ ድንበራቸውም ፡ በምዕ
ራብ ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ መርዓላ ፡ ወጣ ፥ እስከ ፡

ደበሼትም ፡ ደረሰ ፤ በዮቅንዓም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡
፲፪ ወዳለው ፡ ወንዝ ፡ ደረሰ ፤ ከሣሪድም ፡ ወደ ፡
ፀሐይ ፡ መውጫ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ወደ ፡ ኪስ
፲፫ ሎትታቦር ፡ ዳርቻ ፡ ዞረ ፤ ወደ ፡ ዳብራትም ፡
ወጣ ፥ ወደ ፡ ያፊዓም ፡ ደረሰ ፤ ከዚያም ፡ በም
ሥራቅ ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ጋትሔፍርና ፡ ወደ ፡
ዒታቃጺን ፡ አለፈ ፤ ወደ ፡ ሬምንና ፡ ወደ ፡ ኒዓ ፡
፲፬ ወጣ ። ድንበሩም ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ሐና
ቶን ፡ ዞረ ፥ መውጫውም ፡ በይፍታሕኤል ፡
፲፭ ሸለቆ ፡ ነበረ ። ቀጣት ፥ ነህላል ፥ ሺምሮን ፥
ይዳላ ፥ ቤተ ፡ ልሔም ፤ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ከተ
፲፮ ሞችና ፡ መንደሮቻቸው ። የዛብሎን ፡ ልጆች ፡
ርስት ፡ በየወገኖቻቸው ፡ እነዚህ ፡ ከተሞችና ፡
መንደሮቻቸው ፡ ናቸው ።

፲፯ አራተኛውም ፡ ዕጣ ፡ ለይሳኮር ፡ ልጆች ፡ በየወ
፲፰ ገኖቻቸው ፡ ወጣ ። ድንበራቸውም ፡ ወደ ፡ ኢይ
፲፱ ዝራኤል ፥ ወደ ፡ ከስሎት ፥ ወደ ፡ ሱነም ፥ ወደ ፡
ሐፍራይም ፥ ወደ ፡ ሺአን ፥ ወደ ፡ አናሐራት ፥
፳ ወደ ፡ ረቢት ፥ ወደ ፡ ቂሶን ፥ ወደ ፡ አቤጽ ፥
፳፩ ወደ ፡ ሬሜት ፥ ወደ ፡ ዓይንጋኒም ፥ ወደ ፡ ዓይ
፳፪ ንሐዳ ፥ ወደ ፡ ቤትጳጼጽ ፡ ደረሰ ፤ ድንበሩም ፡
ወደ ፡ ታቦርና ፡ ወደ ፡ ሻሕጺማ ፥ ወደ ፡ ቤትሳ
ሚስ ፡ ደረሰ ፥ የድንበራቸውም ፡ መውጫ ፡ ዮር
ዳኖስ ፡ ነበረ ፤ አሥራ ፡ ስድስት ፡ ከተሞችና ፡
፳፫ መንደሮቻቸው ። የይሳኮር ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡
ርስት ፡ በየወገኖቻቸው ፡ እነዚህ ፡ ከተሞችና ፡
መንደሮቻቸው ፡ ናቸው ።

፳፬ አምስተኛውም ፡ ዕጣ ፡ ለአሴር ፡ ልጆች ፡
፳፭ ነገድ ፡ በየወገኖቻቸው ፡ ወጣ ። ድንበራቸውም ፡
፳፮ ሔልቃት ፥ ሐሊ ፥ ቤጤን ፥ አዚፍ ፥ አላሜሌክ ፥
ዓምዓድ ፥ ሚሽአል ፡ ነበረ ፤ በምዕራብ ፡ በኩል ፡
ወደ ፡ ቀርሜሎስና ፡ ወደ ፡ ሺሖርሊብናት ፡ ደረሰ ፤
፳፯ ወደ ፡ ፀሐይም ፡ መውጫ ፡ ወደ ፡ ቤትዳጎን ፡
ዞረ ፥ ወደ ፡ ዛብሎንም ፡ ወደ ፡ ይፍታሕኤል ፡
ሸለቆ ፥ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ቤትዔሜቅና ፡
ወደ ፡ ንዒኤልም ፡ ደረሰ ፡ በስተ ፡ ግራ ፡ በኩልም ፡
፳፰ ወደ ፡ ካቡል ፡ ወጣ ፤ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ዔብሮን ፥
ወደ ፡ ረአብ ፥ ወደ ፡ ሐሞን ፥ ወደ ፡ ቃና ፡ እስከ ፡
፳፱ ታላቁ ፡ ሲዶናም ፡ ደረሰ ። ድንበሩም ፡ ወደ ፡
ራማ ፥ ወደ ፡ ተመሸገውም ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡
ጢሮስ ፡ ዞረ ፤ ድንበሩም ፡ ወደ ፡ ሖሳ ፡ ዞረ ፤
መውጫውም ፡ በአክዚብ ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ባሕሩ ፡
ነበረ ፤ ዑማ ፥ አፌቅ ፥ ረአብ ፡ ደግሞ ፡ ነበሩ ፤
ሀያ ፡ ሁለት ፡ ከተሞችና ፡ መንደሮቻቸው ።
የአሴር ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ርስት ፡ በየወገኖቻቸው ፡
እነዚህ ፡ ከተሞችና ፡ መንደሮቻቸው ፡ ናቸው ።

ስድስተኛውም ፡ ዕጣ ፡ ለንፍታሌም ፡ ልጆች ፡
በየወገኖቻቸው ፡ ወጣ ። ድንበራቸውም ፡ ከሔ
ሌፍ ፥ ከጸዕናኒም ፡ ዛፍ ፥ ከአዳሚኔቄብ ፥ ከየ
ብኒኤል ፡ እስከ ፡ ለቁም ፡ ድረስ ፡ ነበረ ፤ መው
ጫውም ፡ በዮርዳኖስ ፡ ነበረ ። ድንበሩም ፡ ወደ ፡
ምዕራብ ፡ ወደ ፡ አዝኖትታቦር ፡ ዞረ ፥ ከዚያም ፡
ወደ ፡ ሑቆቅ ፡ ወጣ ፤ ከዚያም ፡ በደቡብ ፡
በኩል ፡ ወደ ፡ ዛብሎን ፥ በምዕራብ ፡ በኩል ፡
ወደ ፡ አሴር ፥ በዮርዳኖስም ፡ በፀሐይ ፡ መውጫ ፡
፴፭ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ደረሰ ። የተመሸጉትም ፡ ከተ
ሞች ፡ እነዚህ ፡ ነበሩ ፤ ጺዲም ፥ ጼር ፥ ሐማት ፥
፴፮ ረቃት ፥ ኬኔሬት ፥ አዳማ ፥ ራማ ፥ አሶር ፥
፴፯፡፴፰ ቃዴስ ፥ ኤድራይ ፥ ዓይንሐጾር ፥ ይርአን ፥
ሚግዳልኤል ፥ ሖሬም ፥ ቤትዓናት ፥ ቤትሳ
ሚስ ፤ አሥራ ፡ ዘጠኝ ፡ ከተሞችና ፡ መንደሮ
፴፱ ቻቸው ። የንፍታሌም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ርስት ፡
በየወገኖቻቸው ፡ እነዚህ ፡ ከተሞችና ፡ መንደ
ሮቻቸው ፡ ናቸው ።

፵ ሰባተኛውም ፡ ዕጣ ፡ ለዳን ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡
፵፩ በየወገኖቻቸው ፡ ወጣ ። የርስታቸውም ፡ ዳርቻ ፡
ይህ ፡ ነበረ ፤ ጾርዓ ፥ ኤሽታኦል ፥ ዒርሼሜሽ ፥
፵፪፡፵፫ ሸዕለቢን ፥ ኤሎን ፥ ይትላ ፥ ኤሎን ፥ ተምና ፥
፵፬ አቃሮን ፥ ኢልተቄ ፥ ገባቶን ፥ በዕላት ፥
፵፭፡፵፮ ይሁድ ፥ ብኔብረቅ ፥ ጋትሪሞን ፥ ሜያርቆን ፥
በኢዮጴ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ካለው ፡ ዳርቻ ፡ ጋር ፡
፵፯ ራቆን ። የዳንም ፡ ልጆች ፡ ዳርቻ ፡ አልበቃቸ
ውም ፤ የዳንም ፡ ልጆች ፡ ከሌሼም ፡ ጋር ፡
ሊዋጉ ፡ ወጡ ፥ ያዙአትም ፥ በሰይፍም ፡ ስለት ፡
መቱአት ፥ ወረሱአትም ፥ ተቀመጡባትም ፤
ስምዋንም ፡ በአባታቸው ፡ በዳን ፡ ስም ፡ ዳን ፡
፵፰ ብለው ፡ ጠሩአት ። የዳን ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ርስት ፡
በየወገኖቻቸው ፡ እነዚህ ፡ ከተሞችና ፡ መንደ
ሮቻቸው ፡ ናቸው ።

፵፱ ምድሩንም ፡ ሁሉ ፡ በየድንበሩ ፡ ርስት ፡ እን
ዲሆን ፡ ከፍለው ፡ ከጨረሱ ፡ በኋላ ፥ የእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ ለነዌ ፡ ልጅ ፡ ለኢያሱ ፡ በመካከ
፶ ላቸው ፡ ርስት ፡ ሰጡት ። በኤፍሬም ፡ ተራራማ ፡
አገር ፡ ያለችውን ፡ ተምናሴራ ፡ የምትባለውን ፡
የፈለጋትን ፡ ከተማ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ትእዛዝ ፡ ሰጡት ፤ ከተማም ፡ ሠርቶ ፡ ተቀመ
ጠባት ።

፶፩ ካህኑ ፡ አልዓዛር ፥ የነዌም ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፥
የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ነገዶች ፡ የአባቶች ፡
አለቆች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በሴሎ ፡ በመ
ገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጃፍ ፡ አጠገብ ፡ በዕጣ ፡
የተከፈሉት ፡ ርስት ፡ ይህ ፡ ነው ። ምድሪቱንም ፡
መከፈል ፡ ጨረሱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ኢያሱን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፪፡፫ ተናገረው ፡— ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡
ብለህ ፡ ተናገራቸው ፡— ሳይወድድ ፡ ሳያውቅም ፡
ሰውን ፡ የገደለ ፡ ገዳይ ፡ እንዲሸሸባቸው ፡ በሙሴ ፡
እጅ ፡ የነገርኋችሁን ፡ መማፀኛ ፡ ከተሞችን ፡
ለዩ ፤ ከደም ፡ ተበቃዩ ፡ መማፀኛ ፡ ይሆኑላች
፬ ኋል ። ከእነዚህም ፡ ከተሞች ፡ ወደ ፡ አንዲቱ ፡
ይሸሻል ፥ በከተማይቱም ፡ በር ፡ አደባባይ ፡ ቆሞ ፡
በከተማይቱ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ጆሮ ፡ ነገሩን ፡ ይና
ገራል ፤ እነርሱም ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ ይቀበሉ
ታል ፥ የሚቀመጥበትም ፡ ስፍራ ፡ ይሰጡታል ።
፭ ደም ፡ ተበቃዩ ፡ ቢያሳድደው ፥ አስቀድሞ ፡ ሳይ
ጠላው ፡ ባልንጀራውን ፡ በስሕተት ፡ ስለ ፡ ገደ

ለው ፡ ነፍስ ፡ ገዳዩን ፡ በእጁ ፡ አሳልፈው ፡ አይ ስጡት ። ፮ በማኅበሩ ፡ ፊት ፡ ለፍርድ ፡ እስኪ ቆም ፡ ድረስ ፥ በዚያም ፡ ወራት ፡ ያለው ፡ ታላቁ ፡ ካህን ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ በዚያች ፡ ከተማ ፡ ይቀመጥ ፤ ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ ነፍስ ፡ ገዳዩ ፡ ይመ ለሳል ፥ ወደ ፡ ከተማውም ፡ ወደ ፡ ቤቱም ፡ ሸሽቶ ፡ ወደ ፡ ወጣበትም ፡ ከተማ ፡ ይገባል ።

፯ በንፍታሌም ፡ ባለው ፡ በተራራማው ፡ አገር ፡ በገሊላ ፡ ቃዴስን ፥ በኤፍሬምም ፡ ባለው ፡ በተ ራራማው ፡ አገር ፡ ሴኬምን ፥ በይሁዳም ፡ ባለው ፡ በተራራማው ፡ አገር ፡ ኬብሮን ፡ የምትባለውን ፡ ቂርያትአርባቅን ፡ ለዩ ። ፰ በዮርዳኖስም ፡ ማዶ ፡ ከኢያሪኮ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ከሮቤል ፡ ነገድ ፡ በምድረ ፡ በዳው ፡ በደልዳላው ፡ ስፍራ ፡ ቦሶ ርን ፥ ከጋድም ፡ ነገድ ፡ በገለዓድ ፡ ራሞትን ፥ ከምናሴም ፡ ነገድ ፡ በባሳን ፡ ጎላንን ፡ ለዩ ። ፱ በማ ኅበሩ ፡ ፊት ፡ እስኪቆም ፡ ድረስ ፡ በደም ፡ ተበ ቃዩ ፡ እጅ ፡ እንዳይሞት ፡ ሳያውቅ ፡ ሰውን ፡ የገ ደለ ፡ ወደዚያ ፡ እንዲሸሽ ፥ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ በመካከላቸውም ፡ ለሚቀመጥ ፡ መጻተኛ ፡ የተለዩ ፡ ከተሞች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ የሌዋውያን ፡ አበቶች ፡ አለቆች ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ወደ ፡ አልዓዛር ፥ ወደ ፡ ነዌም ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢያሱ ፥ ወደ ፡ እስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ነገዶች ፡ አለቆች ፡ ቀረቡ ፤ ፪ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ባለችው ፡ በሴሎ ፡ — እግዚአብሔር ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ የም ንቀመጥባቸውን ፡ ከተሞች ፥ ለከብቶቻችንም ፡ መሰምርያዎች ፡ ትሰጡን ፡ ዘንድ ፡ አዝዞአል ፡ ብሰው ፡ ተናገሩአቸው ። ፫ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ ከርስታቸው ፡ እነዚህን ፡ ከተሞችና ፡ መሰምርያቸውን ፡ ለሌ ዋውያን ፡ ሰጡ ።

፬ ለቀዓትም ፡ ወገኖች ፡ ዕጣ ፡ ወጣ ፤ ሌዋውያ ንም ፡ ለነበሩ ፡ ለካህኑ ፡ ለአሮን ፡ ልጆች ፡ ከይ ሁዳ ፡ ነገድ ፥ ከስምዖንም ፡ ነገድ ፥ ከብንያምም ፡ ነገድ ፡ አሥራ ፡ ሦስት ፡ ከተሞች ፡ በዕጣ ፡ ሆኑ ላቸው ።

፭ ለቀሩትም ፡ ለቀዓት ፡ ልጆች ፡ ከኤፍሬም ፡ ነገድ ፥ ከዳንም ፡ ነገድ ፥ ከምናሴም ፡ ነገድ ፡ እኩ ሌታ ፡ አሥር ፡ ከተሞች ፡ በዕጣ ፡ ሆኑላቸው ።

፮ ለጌድሶንም ፡ ልጆች ፡ ከይሳኮር ፡ ነገድ ፥ ከአ ሴርም ፡ ነገድ ፥ ከንፍታሌምም ፡ ነገድ ፥ በባሳ ንም ፡ ካለው ፡ ከምናሴ ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ አሥራ ፡ ሦስት ፡ ከተሞች ፡ በዕጣ ፡ ሆኑላቸው ።

፯ ለሜራሪም ፡ ልጆች ፡ በየወገኖቻቸው ፡ ከሮ ቤል ፡ ነገድ ፥ ከጋድም ፡ ነገድ ፥ ከዛብሎንም ፡ ነገድ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ከተሞች ፡ ሆኑላቸው ።

፰ እግዚአብሔርም ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ እንዳዘዘ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እነዚህን ፡ ከተሞችና ፡ መሰምርያቸውን ፡ ለሌዋውያን ፡ በዕጣ ፡ ሰጡ ። ፱ ከይሁዳም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ ከስምዖንም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ፡ በስማቸው ፡ የተጠሩትን ፡ እነዚህን ፡ ከተ ሞች ፡ ሰጡ ። ፲ የፊተኛው ፡ ዕጣ ፡ ለእነርሱ ፡ ስለ ፡ ወጣ ፡ የሌዊ ፡ ልጆች ፡ የቀዓት ፡ ወገን ፡ ለሆኑ ፡ ለአሮን ፡ ልጆች ፡ ሆኑ ። ፲፩ በይሁዳ ፡ ተራራማ ፡ አገር ፡ ያለችውን ፡ ቂርያትአርባቅ ፡ የምትባለ ውን ፡ ከተማ ፡ በዙሪያዋም ፡ ያለውን ፡ መሰም ርያ ፡ ሰጡአቸው ፤ አርስዋም ፡ ኬብሮን ፡ ናት ፥ ይህም ፡ አርባቅ ፡ የዔናቅ ፡ አባት ፡ ነበረ ። ፲፪ የከ ተማይቱን ፡ እርሻ ፡ ግን ፡ መንደሮችዋንም ፡ ለዮ ፎኒ ፡ ልጅ ፡ ለካሌብ ፡ ርስት ፡ አድርገው ፡ ሰጡት ።

፲፫ ለካህኑም ፡ ለአሮን ፡ ልጆች ፡ እነዚህን ፡ ሰጡ ፤ ለነፍስ ፡ ገዳይ ፡ መማፀኛ ፡ ከተማ ፡ የሆነችውን ፡ ኬብሮንንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ልብናንና ፡ መሰ ምርያዋን ፥ ፲፬ የቲርንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ኤሽት ሞዓንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ፲፭ ሖሎንንና ፡ መሰምር ያዋን ፥ ፲፮ ዳቤርንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ዓይንንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ዮጣንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ቤት ሳሚስንና ፡ መሰምርያዋን ፤ ከእነዚህ ፡ ከሁለቱ ፡ ነገዶች ፡ ዘጠኝ ፡ ከተሞችን ፡ ሰጡ ። ፲፯ ከብንያ ምም ፡ ነገድ ፡ ገባዖንንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ናሲ ብንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ፲፰ ዓናቶትንና ፡ መሰምር ያዋን ፥ አልሞንንና ፡ መሰምርያዋን ፤ አራት ፡ ከተሞችን ፡ ሰጡ ። ፲፱ የአሮን ፡ ልጆች ፡ የካህናት ፡ ከተሞች ፡ ከመሰምርያቸው ፡ ጋር ፡ አሥራ ፡ ሦስት ፡ ናቸው ።

፳ ለቀሩትም ፡ ለቀዓት ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ ሌዋው ያን ፡ የዕጣቸው ፡ ከተሞች ፡ ከኤፍሬም ፡ ነገድ ፡ ደረሱአቸው ። ፳፩ በኤፍሬም ፡ ተራራማ ፡ አገር ፡ ለነፍስ ፡ ገዳይ ፡ መማፀኛ ፡ ከተማ ፡ የሆነችውን ፡ ሴኬምንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ጌዝርንና ፡ መሰም ርያዋን ፥ ፳፪ ቂብጻይምንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ቤት ሖሮንንና ፡ መሰምርያዋን ፤ አራቱን ፡ ከተሞች ፡ ሰጡአቸው ። ፳፫ ከዳንም ፡ ነገድ ፡ ኤልተቄንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ገባቶንንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ፳፬ ኤሎንንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ጋትሪሞንንና ፡ መሰ ምርያዋን ፤ አራቱን ፡ ከተሞች ፡ ሰጡአቸው ። ፳፭ ከምናሴም ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ታዕናክንና ፡ መሰ ምርያዋን ፥ ጋትሪሞንንና ፡ መሰምርያዋን ፤ ሁለ ቱን ፡ ከተሞች ፡ ሰጡአቸው ። ፳፮ የቀሩት ፡ የቀ ዓት ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ከመ ሰምርያቸው ፡ ጋር ፡ አሥር ፡ ናቸው ።

፳፯ ለሌዋውያንም ፡ ወገኖች ፡ ለጌድሶን ፡ ልጆች ፡ ከምናሴ ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ለነፍስ ፡ ገዳይ ፡ መማፀኛ ፡ ከተማ ፡ በባሳን ፡ ውስጥ ፡ የሆነች ውን ፡ ጎላንንና ፡ መሰምርያዋን ፥ በኤሽትራ ንና ፡ መሰምርያዋን ፤ ሁለቱን ፡ ከተሞች ፡ ሰጡ አቸው ። ፳፰ ከይሳኮርም ፡ ነገድ ፡ ቂሶንንና ፡ መሰም ርያዋን ፥ ፳፱ ዳብራትንና ፡ መሰምርያዋን ፥ የርሙ ትንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ዓይንጋኒምንና ፡ መሰ ምርያዋን ፤ አራቱን ፡ ከተሞች ፡ ሰጡአቸው ። ፴ ከአሴርም ፡ ነገድ ፡ ሚሽአልንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ዓብዶንንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ፴፩ ሔልቃትንና ፡ መሰ ምርያዋን ፥ ረአብንና ፡ መሰምርያዋን ፤ አራቱን ፡ ከተሞች ፡ ሰጡአቸው ። ፴፪ ከንፍታሌምም ፡ ነገድ ፡ ለነፍስ ፡ ገዳይ ፡ መማፀኛ ፡ ከተማ ፡ የሆነችውን ፡

በገሊላ ፡ ውስጥ ፡ ቃዴስንና ፡ መሰምርያዋን ፥
ሐሞትዶርንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ቀርታንንና ፡
መሰምርያዋን ፤ ሦስቱን ፡ ከተሞች ፡ ሰጡአቸው ።
፴፫ ፤ የጌድሶን ፡ ልጆች ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ በየወገኖ
ቻቸው ፡ አሥራ ፡ ሦስት ፡ ከተሞች ፡ ከመሰምር
ያቸው ፡ ጋር ፡ ናቸው ።
፴፬ ፤ ከሌዋውያንም ፡ ለቀሩት ፡ ለሜራሪ ፡ ልጆች ፡
ወገን ፡ ከዛብሎን ፡ ነገድ ፡ ዮቅንዓምንና ፡ መሰ
፴፭ ፤ ምርያዋን ፥ ቀርታንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ዲሞ
ናንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ነህላልንና ፡ መሰምርያ
፴፮ ፤ ዋን ፤ አራቱን ፡ ከተሞች ፡ ሰጡ ። ከሮቤልም ፡
ነገድ ፡ ቦሶርንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ያህጽንና ፡
፴፯ ፤ መሰምርያዋን ፥ ቅዴሞትንና ፡ መሰምርያዋን ፥
ሜፍዓትንና ፡ መሰምርያዋን ፤ አራቱን ፡ ከተ
፴፰ ፤ ሞች ፡ ሰጡ ። ከጋድም ፡ ነገድ ፡ ለነፍሰ ፡ ገዳይ ፡
መማፀኛ ፡ ከተማ ፡ የሆነችውን ፡ በገለዓድ ፡
ውስጥ ፡ ራሞትንና ፡ መሰምርያዋን ፥ መሃናይ
፴፱ ፤ ምንና ፡ መሰምርያዋን ፥ ሐሴቦንንና ፡ መሰምር
ያዋን ፥ ኢያዜርንና ፡ መሰምርያዋን ፤ አራቱን ፡
፵ ፤ ከተሞች ፡ ሰጡ ። ከሌዋውያን ፡ ወገኖች ፡ የቀ
ሩት ፡ የሜራሪ ፡ ልጆች ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ በየ
ወገኖቻቸው ፡ እነዚህ ፡ ነበሩ ፤ ዕጣቸውም ፡
አሥራ ፡ ሁለት ፡ ከተማ ፡ ነበረ ።
፵፩ ፤ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡ መካከል ፡ የነበ
ሩት ፡ የሌዋውያን ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ አርባ ፡ ስም
፵፪ ፤ ንት ፡ ከተሞችና ፡ መሰምርያቸው ፡ ነበሩ ። እነ
ዚህም ፡ ከተሞች ፡ እያንዳንዳቸው ፡ ከመሰምር
ያቸው ፡ ጋር ፡ ነበሩ ፤ እነዚህም ፡ ከተሞች ፡
ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ ነበሩ ።
፵፫ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ለአባ
ቶቻቸው ፡ የማለላቸውን ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ለእ
ስራኤል ፡ ሰጠ ፤ ወረሱአትም ፥ ተቀመጡበ
፵፬ ፤ ትም ። እግዚአብሔርም ፡ ለአባቶቻቸው ፡ እንደ ፡
ማለላቸው ፡ በዙሪያቸው ፡ ካሉት ፡ አሳረፋቸው ፤
ከጠላቶቻቸውም ፡ ሁሉ ፡ ይቋቋማቸው ፡ ዘንድ ፡
ማንም ፡ ሰው ፡ አልቻለም ፤ እግዚአብሔርም ፡
ጠላቶቻቸውን ፡ ሁሉ ፡ በእጃቸው ፡ አሳልፎ ፡
፵፭ ፤ ሰጣቸው ። እግዚአብሔር ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡
ከተናገረው ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ተፈጸመ ፡
እንጂ ፡ ምንም ፡ አልቀረም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ ፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኢያሱ ፡ የሮቤልን ፡ ልጆችና ፡
የጋድን ፡ ልጆች ፡ የምናሴንም ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡
፪ ፤ ጠርቶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— የእግዚአብሔር ፡
ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ ያዘዛችሁን ፡ ሁሉ ፡ ጠብቃችኋል ፥
እኔም ፡ ላዘዝኋችሁ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ታዝዛችኋል ፤
፫ ፤ ይህንም ፡ ያህል ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡
ድረስ ፡ ወንድሞቻችሁን ፡ አልተዋችሁም ፥
የአምላካችሁንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡
፬ ፤ ጠብቃችኋል ። አሁንም ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንደ ፡ ተናገራቸው ፡ ወንድሞቻች
ሁን ፡ አሳርፎአቸዋል ፤ አሁን ፡ እንግዲህ ፡
ተመለሱ ፥ ወደ ፡ ቤታችሁና ፡ የእግዚአብሔር ፡
ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ወደ ፡ ሰጣችሁ ፡
፭ ፤ ወደ ፡ ርስታችሁ ፡ ምድር ፡ ሂዱ ። ብቻ ፡ የእግ
ዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ ያዘዛችሁን ፡ ትእዛ
ዙንና ፡ ሕጉን ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፥ አምላካች
ሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትወድዱ ፡ ዘንድ ፥ መንገ
ዱንም ፡ ሁሉ ፡ ትሄዱ ፡ ዘንድ ፥ ትእዛዙንም ፡
ትጠብቁ ፡ ዘንድ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ትጠጉ ፡
ዘንድ ፥ በፍጹምም ፡ ልባችሁ ፡ በፍጹምም ፡
ነፍሳችሁ ፡ ታመልኩ ፡ ዘንድ ፡ እጅግ ፡ ተጠን
፮ ፤ ቀቁ ። ኢያሱም ፡ መረቃቸው ፥ ሰደዳቸውም ፤
ወደ ፡ ቤታቸውም ፡ ሄዱ ።
፯ ፤ ለምናሴም ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ሙሴ ፡ በባሳን ፡
ውስጥ ፡ ርስት ፡ ሰጥቶአቸው ፡ ነበር ፤ ለቀ
ረው ፡ ለእኩሌታው ፡ ግን ፡ ኢያሱ ፡ በዮር
ዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በምዕራብ ፡ ወገን ፡ በወንድ
ሞቻቸው ፡ መካከል ፡ ርስት ፡ ሰጣቸው ። ኢያ
ሱም ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ በሰደዳቸው ፡ ጊዜ ፡
፰ ፤ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ መረቃቸው ፡—— በብዙ ፡
ብልጥግና ፡ በእጅግም ፡ ብዙ ፡ ከብት ፥ በብ
ርም ፥ በወርቅም ፥ በናስም ፥ በብረትም ፥
በእጅግም ፡ ብዙ ፡ ልብስ ፡ ወደ ፡ ቤታችሁ ፡
ተመለሱ ፤ የጠላቶቻችሁንም ፡ ምርኮ ፡ ከወን
ድሞቻችሁ ፡ ጋር ፡ ተካፈሉ ።
፱ ፤ የሮቤልም ፡ ልጆች ፡ የጋድም ፡ ልጆች ፡ የም
ናሴም ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ሄዱ ፤ በሙሴም ፡ እጅ ፡
በተሰጠ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ ወደ ፡
ተቀበሉአት ፡ ወደ ፡ ርስታቸው ፡ ወደ ፡ ገለዓድ ፡
ምድር ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ካለ
ችው ፡ ከሴሎ ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡
፲ ፤ ተመለሱ ። በከነዓን ፡ ምድር ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡
ዮርዳኖስ ፡ አቅራቢያም ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ የሮ
ቤል ፡ ልጆችና ፡ የጋድ ፡ ልጆች ፡ የምናሴም ፡
ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ በዚያ ፡ በዮርዳኖስ ፡ አጠገብ ፡
፲፩ ፤ ታላቅ ፡ መሠዊያ ፡ ሠሩ ። ለእስራኤልም ፡
ልጆች ፡— እነሆ ፥ በከነዓን ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡
በዮርዳኖስ ፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡ ግዛት ፥ የእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ ባሉበት ፡ ወገን ፥ የሮቤል ፡
ልጆችና ፡ የጋድ ፡ ልጆች ፡ የምናሴም ፡ ነገድ ፡
እኩሌታ ፡ መሠዊያ ፡ ሠርተዋል ፡ የሚል ፡
፲፪ ፤ ወሬ ፡ ደረሰላቸው ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
ይህን ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ወጥተው ፡ እነርሱን ፡ ሊዋጉ ፡
በሴሎ ፡ ተሰበሰቡ ።
፲፫ ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በገለዓድ ፡ ምድር ፡
ወዳሉት ፡ ወደ ፡ ሮቤል ፡ ልጆችና ፡ ወደ ፡
ጋድ ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ምናሴም ፡ ነገድ ፡ እኩ
ሌታ ፡ የካህኑን ፡ የአልዓዛርን ፡ ልጅ ፡ ፊንሐ
፲፬ ፤ ስን ፡ ላኩ ። ከእርሱም ፡ ጋር ፡ አሥር ፡ አለ
ቆች ፡ ነበሩ ፥ ከእስራኤል ፡ ከየነገዱ ፡ ሁሉ ፡
አንድ ፡ አንድ ፡ የአባቶች ፡ ቤት ፡ አለቃ ፤
እያንዳንዱም ፡ በእስራኤል ፡ አእላፋት ፡ መካ
ከል ፡ የእየአባቶቻቸው ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡
፲፭ ፤ ነበረ ። በገለዓድም ፡ ምድር ፡ ወዳሉት ፡ ወደ ፡
ሮቤል ፡ ልጆችና ፡ ወደ ፡ ጋድ ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡

ምናሴም ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ መጡ ፡ እንዲህም ፡
፲፮ ብለው ፡ ተናገሩአቸው ፡ — የእግዚአብሔር ፡ ማኅ
በር ፡ ሁሉ ፡ የሚለው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ — ይህ ፡ በእ
ስራኤል ፡ አምላክ ፡ ላይ ፡ ያደረጋችሁት ፡ ኃጢ
አት ፡ ምንድር ፡ ነው ? ዛሬ ፡ እግዚአብሔርን ፡
ከመከተል ፡ ተመልሳችኋል ፤ ዛሬም ፡ መሠዊያ ፡
በመሥራታችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ዐም
፲፯ ፀችኋል ። እኛ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ከእርሱ ፡
ያልነጻንበት ፡ የፌጎር ፡ ኃጢአት ፡ ጥቂት ፡
ነውን ? በእግዚአብሔር ፡ ማኅበር ፡ ላይ ፡ መቅ
፲፰ ሠፍት ፡ ወረደ ። እናንተ ፡ ዛሬ ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ ከመከተል ፡ ትመለሳላችሁን ? ዛሬ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ብታምፁ ፡ ነገ ፡ በእስራኤል ፡
፲፱ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ይቈጣል ። ነገር ፡ ግን ፡
የርስታችሁ ፡ ምድር ፡ የረከሰ ፡ ቢመስላችሁ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ወደሚቀመጥበት ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ርስት ፡ ምድር ፡ አልፋ
ችሁ ፡ በመካከላችን ፡ ውረሱ ፤ ከአምላካችንም ፡
ከእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ሌላ ፡ ለእናንተ ፡
መሠዊያ ፡ በመሥራታችሁ ፡ በእግዚአብሔርና ፡
፳ በእኛ ፡ ላይ ፡ አታምፁ ። የዛራ ፡ ልጅ ፡ አካን ፡
እርም ፡ ነገር ፡ በመውሰድ ፡ ኃጢአትን ፡ ስለ ፡
ሠራ ፡ በእስራኤል ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ቍጣ ፡
አልወረደምን ? እርሱም ፡ በኃጢአቱ ፡ ብቻ
ውን ፡ አልሞተም ።

፳፩ የሮቤል ፡ ልጆችና ፡ የጋድ ፡ ልጆች ፡ የምና
ሴም ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ለእስራኤል ፡ አእላፋት ፡
አለቆች ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ መለሱላቸው ፡ —
፳፪ የአማልክት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ÷ የአማ
ልክት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እርሱ ፡ አው
ቆታል ÷ እስራኤልም ፡ ያውቀዋል ፤ በእግዚ
አብሔር ፡ ላይ ፡ ዐምፀንና ፡ ተላልፈን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
፳፫ ዛሬ ፡ አታድነን ፤ እግዚአብሔርን ፡ ከመከተል ፡
እንድንመለስ ÷ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡
የእህልን ፡ ቍርባን ፡ እንድናሳርግበት ÷ የደኅን
ነትንም ፡ መሥዋዕት ፡ እንድናቀርብበት ፡ ብለን ፡
መሠዊያ ፡ ሠርተን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እግዚአብሔር ፡
፳፬ እርሱ ፡ ራሱ ፡ ይበቀለን ፤ ይልቁንም ፡ ከልባ
ችን ፡ ፍርሃት ፡ የተነሣ ፡ — በሚመጣው ፡ ዘመን ፡
ልጆቻችሁ ፡ ልጆቻችንን ፡ — ከእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አላችሁ ?
፳፭ እናንተ ፡ የሮቤልና ፡ የጋድ ፡ ልጆች ÷ እግዚአ
ብሔር ፡ በእኛና ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡ ዮርዳኖ
ስን ፡ ድንበር ፡ አድርጎአልና ፡ በእግዚአብሔር ፡
ዘንድ ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ የላችሁም ፡ ይሉአቸ
ዋል ፡ ብለን ፡ ይህን ፡ አደረግን ። በዚህም ፡
ልጆቻችሁ ፡ ልጆቻችንን ፡ እግዚአብሔርን ፡
፳፮ ከመፍራት ፡ ያስተዋቸዋል ። ስለዚህም ፡ —
መሠዊያ ፡ እንሥራ ፡ አልን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለሚ
ቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ወይም ፡ ለሌላ ፡ መሥዋ
፳፯ ዕት ፡ አይደለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በእኛና ፡ በእና
ንተ ፡ መካከል ፡ ከእኛም ፡ በኋላ ፡ በትውልዳች
ንና ፡ በትውልዳችሁ ፡ መካከል ፡ በሚቃጠል ፡
መሥዋዕትና ፡ በቍርባን ፡ በደኅንነትም ፡ መሥ
ዋዕታችን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እናመልክ ፡ ዘንድ ÷
በሚመጣውም ፡ ዘመን ፡ ልጆቻችሁ ፡ ልጆቻች
ንን ፡ — በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡
፳፰ የላችሁም ፡ እንዳይሉ ፡ ምስክር ፡ ይሆናል ። ስለ
ዚህም ፡ አልን ፡ — በሚመጣው ፡ ዘመን ፡ ለእኛ ፡
ወይም ፡ ለትውልዳችን ፡ ይህን ፡ ሲሉ ÷ እኛ ፡ —
እነሆ ÷ አባቶቻችን ፡ ያደረጉትን ፡ የእግዚአብ
ሔርን ፡ መሠዊያ ፡ ምሳሌ ፡ እዩ ፤ በእኛና ፡ በእ
ናንተ ፡ መካከል ፡ ምስክር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ስለ
ሚቃጠል ፡ መሥዋዕትና ፡ ስለ ፡ ሌላ ፡ መሥዋ
፳፱ ዕት ፡ አይደለም ፡ እንላለን ። በማደሪያው ፡
ፊት ፡ ካለው ፡ ከአምላካችን ፡ ከእግዚአብሔር ፡
መሠዊያ ፡ ሌላ ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕትና ፡
ለእህል ፡ ቍርባን ፡ ለሌላ ፡ መሥዋዕትም ፡ የሚ
ሆን ፡ መሠዊያን ፡ የሠራነው ፡ በእግዚአብሔር ፡
ላይ ፡ በማመፅ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ዛሬ ፡ መከ
ተልን ፡ ለመተው ፡ በማለት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይህ ፡
ከእኛ ፡ ይራቅ ።

፴ ካህኑ ፡ ፊንሐስና ፡ የማኅበሩ ፡ አለቆች ÷ ከእ
ርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ የእስራኤል ፡ አእላፋት ፡
አለቆች ÷ የሮቤል ፡ ልጆችና ፡ የጋድ ፡ ልጆች ፡
የምናሴም ፡ ልጆች ፡ የተናገሩትን ፡ ቃል ፡ በሰሙ ፡
፴፩ ጊዜ ፡ ነገሩ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አሰኛቸው ። የካህኑም ፡
የአልዓዛር ፡ ልጅ ፡ ፊንሐስ ፡ ለሮቤል ፡ ልጆችና ፡
ለጋድ ፡ ልጆች ፡ ለምናሴም ፡ ልጆች ፡ — ይህን ፡
መተላለፍ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ አላደረጋ
ችሁምና ፤ እግዚአብሔር ፡ በመካከላችን ፡ እን
ዳለ ፡ ዛሬ ፡ እናውቃለን ፤ አሁን ፡ የእስራኤልን ፡
ልጆች ፡ ከእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ አድናችኋል ፡
፴፪ አላቸው ። የካህኑም ፡ የአልዓዛር ፡ ልጅ ፡ ፊን
ሐስና ፡ አለቆቹ ፡ ከሮቤል ፡ ልጆችና ፡ ከጋድ ፡
ልጆች ፡ ዘንድ ፡ ከገለዓድ ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ከነዓን ፡
አገር ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተመለሱ ÷
፴፫ ወሬም ፡ አመጡላቸው ። ነገሩም ፡ የእስራኤ
ልን ፡ ልጆች ፡ ደስ ፡ አሰኘ ፤ የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰገኑ ÷ ከዚያም ፡
ወዲያ ፡ የሮቤል ፡ ልጆችና ፡ የጋድ ፡ ልጆች ፡ የተ
ቀመጡባትን ፡ ምድር ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ ወጥ
፴፬ ተው ፡ እንዲወጉአቸው ፡ አልተናገሩም ። የሮ
ቤል ፡ ልጆችና ፡ የጋድ ፡ ልጆችም ፡ — እግዚአብ
ሔር ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይህ ፡ በመካከላችን ፡
ምስክር ፡ ነው ፡ ሲሉ ፡ መሠዊያውን ፡ ምስክር ፡
ብለው ፡ ጠሩት ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ከሆነ ፡ በኋላ ÷
እግዚአብሔርም ፡ እስራኤልን ፡ በዙሪያቸው ፡
ካሉት ፡ ጠላቶቻቸው ፡ ሁሉ ፡ ካሳረፈ ፡ በኋላ ÷
ኢያሱም ፡ በሸመገለ ፡ በዕድሜውም ፡ ባረጀ ፡
፪ ጊዜ ÷ ኢያሱ ፡ እስራኤልን ፡ ሁሉ ፡ ሽማግሌዎ
ቻቸውንም ፡ አለቆቻቸውንም ፡ ፈራጆቻቸው
ንም ፡ ሹማምቶቻቸውንም ፡ ጠርቶ ፡ እንዲህ ፡
አላቸው ፡ — እኔ ፡ ሸምግያለሁ ÷ በዕድሜም ፡
፫ አርጅቻለሁ ፤ እናንተም ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚ

አብሔር ፡ በእነዚህ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ እና
ንተ ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፡ አይታችኋል ፤ ስለ ፡
እናንተ ፡ የተዋጋ ፡ እርሱ ፡ አምላካችሁ ፡ እግ
፬ ዚአብሔር ፡ ነው ። እነሆ ፥ እኔ ፡ ከጠፉኋቸው ፡
አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ከዮርዳኖስ ፡ ጀምሮ ፡ በፀ
ሐይ ፡ መግቢያ ፡ እስካለው ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡
ባሕር ፡ ድረስ ፡ ለነገዶቻችሁ ፡ ርስት ፡ እንዲ
ሆኑ ፡ የቀሩትን ፡ እነዚህን ፡ አሕዛብ ፡ በዕጣ ፡
፭ ከፈልሁላችሁ ። አምላካችሁም ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እርሱ ፡ ከፊታችሁ ፡ በብርቱ ፡ ይበትናቸ
ዋል ፥ ከፊታችሁም ፡ ያሳድዳቸዋል ፤ አምላክ
ችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተናገራችሁም ፡
፮ ምድራቸውን ፡ ትወርሳላችሁ ። ስለዚህም ፡
በሙሴ ፡ ሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈውን ፡ ሁሉ ፡
ለመጠበቅና ፡ ለማድረግ ፡ በጣም ፡ በርቱ ፥ ከእ
ርሱም ፡ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ ፈቀቅ ፡
፯ አትበሉ ። በእናንተ ፡ መካከል ፡ ወደ ፡ ቀሩት ፡
ወደ ፡ እነዚህ ፡ አሕዛብ ፡ አትግቡ ፤ የአማልክ
ቶቻቸውንም ፡ ስም ፡ አትጥሩ ፥ አትማሉብ
ቸውም ፥ አታምልኩአቸውም ፥ አትስገዱላቸ
፰ ውም ፤ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እንዳደረጋችሁት ፡
ወደ ፡ አምላካችሁ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
፱ ተጠጉ ፡ እንጂ ። እግዚአብሔር ፡ ታላላቆች
ንና ፡ ኃይለኞችን ፡ አሕዛብ ፡ ከፊታችሁ ፡ አስወ
ጥቶአል ፤ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ ማንም ፡ ሊቋ
፲ ቋማችሁ ፡ አልቻለም ። አምላካችሁ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ እንደ ፡ ተናገራችሁ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡
የሚዋጋ ፡ እርሱ ፡ ነውና ፡ ከእናንተ ፡ አንዱ ፡
፲፩ ሰው ፡ ሺህ ፡ ሰውን ፡ ያሳድዳል ። አምላካችሁን ፡
እግዚአብሔርን ፡ ትወድዱት ፡ ዘንድ ፡ ለራሳ
፲፪ ችሁ ፡ እጅግ ፡ ተጠንቀቁ ። እናንተ ፡ ግን ፡ ተመ
ልሳችሁ ፡ በመካከላችሁ ፡ ወደ ፡ ቀሩት ፡ ወደ ፡
እነዚህ ፡ አሕዝብ ፡ ብትጠጉ ፥ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡
ብትጋቡ ፥ እናንተም ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ እነር
፲፫ ሱም ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ብትደራረሱ ፥ አምላ
ካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሰጣችሁ ፡ ከዚህች ፡
ከመልካሚቱ ፡ ምድር ፡ እስክትጠፉ ፡ ድረስ ፡
መውደቂያና ፡ ወጥመድ ፥ በጎናችሁም ፡ መግ
ረፊያ ፥ በዓይኖቻችሁም ፡ እሾህ ፡ ይሆኑባችኋል ፡
እንጂ ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእንግ
ዲህ ፡ ወዲያ ፡ እነዚህን ፡ አሕዛብ ፡ ከፊታችሁ ፡
እንዳያሳድዳቸው ፡ ፈጽማችሁ ፡ እወቁ ።
፲፬ እነሆም ፥ ዛሬ ፡ የምድርን ፡ ሁሉ ፡ መንገድ ፡
እሄዳለሁ ፤ እናንተም ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡
እናንተ ፡ ከተናገረው ፡ ከመልካም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡
አንድ ፡ ነገር ፡ እንዳልቀረ ፡ በልባችሁ ፡ ሁሉ ፡
በነፍሳችሁም ፡ ሁሉ ፡ እወቁ ፤ ሁሉ ፡ ደርሶላች
ኋል ፤ ከእርሱም ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ አልቀረም ።
፲፭ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ የተናገረው ፡ መል
ካም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ደረሰላችሁ ፥ አምላ
ካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሰጣችሁ ፡ ከዚህች ፡
ከመልካሚቱ ፡ ምድር ፡ እናንተን ፡ እስኪያጠፋ
ችሁ ፡ ድረስ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲሁ ፡ ክፉን ፡
፲፮ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ያመጣባችኋል ። አምላካችሁ ፡
እግዚአብሔር ፡ ያዘዛችሁን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ስታ
ፈርሱ ፥ ሄዳችሁም ፡ ሌሎችን ፡ አማልክት ፡ ስታ
መልኩ ፥ ስትሰግዱላቸውም ፥ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ የእ
ግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ ይነድድባችኋል ፥ ከሰጣች
ሁም ፡ ከመልካሚቱ ፡ ምድር ፡ ፈጥናችሁ ፡ ትጠ
ፋላችሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ ኢያሱም ፡ የእስራኤልን ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡
ሴኬም ፡ ሰበሰበ ፥ የእስራኤልንም ፡ ሽማግሌ
ዎች ፡ አለቆቻቸውንም ፡ ፈራጆቻቸውንም ፡
ሹማምቶቻቸውንም ፡ ጠራ ። እነርሱም ፡ በእ
፪ ግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቆሙ ። ኢያሱም ፡ ለሕ
ዝቡ ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— አባቶ
ቻችሁ ፥ የአብርሃምና ፡ የናኮር ፡ አባት ፡ ታራ ፥
አስቀድመው ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ተቀመጡ ፤ ሌሎ
፫ ችንም ፡ አማልክት ፡ አመለኩ ። አባታችሁንም ፡
አብርሃምን ፡ ከወንዝ ፡ ማዶ ፡ ወስጄ ፡ በከነዓን ፡
ምድር ፡ ሁሉ ፡ መራሁት ፤ ዘሩንም ፡ አበዛሁ ፥
፬ ይስሐቅንም ፡ ሰጠሁት ። ለይስሐቅም ፡ ያዕቆ
ብንና ፡ ዔሳውን ፡ ሰጠሁት ፤ ለዔሳውም ፡ የሴ
ይርን ፡ ተራራ ፡ ርስት ፡ አድርጌ ፡ ሰጠሁት ፤ ያዕ
፭ ቆብም ፡ ልጆቹም ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ወረዱ ። ሙሴ
ንና ፡ አሮንንም ፡ ላክሁ ፥ በመካከላቸውም ፡
እንዳደረግሁ ፡ ግብፅን ፡ ቀሠፍሁ ፤ ከዚያም ፡
፮ በኋላ ፡ አወጣኋችሁ ። አባቶቻችሁንም ፡ ከግ
ብፅ ፡ አወጣኋቸው ፥ ወደ ፡ ባሕሩም ፡ ደረሳችሁ ፤
ግብፃውያንም ፡ አባቶቻችሁን ፡ በሰረገሎችና ፡
በፈረሰኞች ፡ እስከ ፡ ኤርትራ ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፡ አባ
፯ ረሩአቸው ። ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በጮኹ ፡
ጊዜ ፡ በእናንተና ፡ በግብፃውያን ፡ መካከል ፡
ጨለማ ፡ አደረገ ፥ ባሕሩንም ፡ መለሰባቸው ፥
አሰጠማቸውም ፤ ዓይኖቻችሁም ፡ በግብፅ ፡ ያደ
ረግሁትን ፡ አዩ ፤ በምድረ ፡ በዳም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡
፰ ተቀመጣችሁ ። እኔም ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ወደ ፡
ተቀመጡበት ፡ ወደ ፡ አሞራውያን ፡ ምድር ፡
አመጣኋችሁ ፤ ከእናንተም ፡ ጋር ፡ ተዋጉ ፥
አሳልፌም ፡ በእጃችሁ ፡ ሰጠኋችሁ ፥ ምድራቸ
ውንም ፡ ወረሳችሁ ፤ ከፊታችሁም ፡ አጠፋኋ
፱ ቸው ። የሞዓብም ፡ ንጉሥ ፡ የሴፎር ፡ ልጅ ፡
ባላቅ ፡ ተነሥቶ ፡ ከእስራኤል ፡ ጋር ፡ ተዋጋ ፤
እንዲረግማችሁም ፡ የቢዖርን ፡ ልጅ ፡ በለዓምን ፡
፲ ልኮ ፡ አስጠራው ። እኔ ፡ ግን ፡ በለዓምን ፡ መስ
ማት ፡ አልወደድሁም ፤ እርሱም ፡ ፈጽሞ ፡ ባረ
፲፩ ካችሁ ፥ እኔም ፡ ከእጁ ፡ አዳንኋችሁ ። ዮርዳ
ኖስንም ፡ ተሻገራችሁ ፥ ወደ ፡ ኢያሪኮም ፡ መጣ
ችሁ ፤ የኢያሪኮም ፡ ሰዎች ፥ አሞራዊው ፥ ፌር
ዛዊው ፥ ከነዓናዊው ፥ ኬጢያዊው ፥ ገርጌሳ
ዊው ፥ ኤዊያዊው ፥ ኢያቡሳዊው ፡ ተዋጉአ
ችሁ ፤ አሳልፌም ፡ በእጃችሁ ፡ ሰጠኋቸው ።
፲፪ በፊታችሁም ፡ ተርብ ፡ ሰደድሁ ፥ በሰይፍህም ፡
በቀስትህም ፡ ሳይሆን ፡ ሁለቱን ፡ የአሞራውያ
ንን ፡ ነገሥታት ፡ ከፊታችሁ ፡ አሳደዳቸው ።

፲፫፤ ያልደከማችሁበትንም ፡ ምድር ፥ ያልሠራችኋቸውንም ፡ ከተሞች ፡ ሰጠኋችሁ ፥ ተቀመጣችሁባቸውም ፤ ካልተከላችኋቸውም ፡ ከወይንና ፡ ከወይራ ፡ በላችሁ ።

፲፬፤ አሁንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፍሩ ፥ በፍጹምም ፡ በእውነተኛም ፡ ልብ ፡ አምልኩት ፤ አባቶቻችሁም ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ በግብፅም ፡ ውስጥ ፡ ያመለኩአቸውን ፡ አማልክት ፡ ከእናንተ ፡ አርቁ ፥ ፲፭፤ እግዚአብሔርንም ፡ አምልኩ ። እግዚአብሔርንም ፡ ማምለክ ፡ ክፉ ፡ መስሎ ፡ ቢታያችሁ ፥ አባቶቻችሁ ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ሳሉ ፡ ያመለኩአቸውን ፡ አማልክት ፡ ወይም ፡ በምድራቸው ፡ ያላችሁባቸውን ፡ የአሞራውያንን ፡ አማልክት ፡ ታመልኩ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ የምታመልኩትን ፡ ዛሬ ፡ ምረጡ ። እኔና ፡ ቤቴ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እናመልካለን ።

፲፮፤ ሕዝቡም ፡ መልሰው ፡ እንዲህ ፡ አሉ ፦ እግዚአብሔርን ፡ ትተን ፡ ሌሎች ፡ አማልክትን ፡ ማምለክ ፡ ከእኛ ፡ ይራቅ ፤ ፲፯፤ እኛንና ፡ አባቶቻችንን ፡ ከባርነት ፡ ቤት ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣን ፥ በዓይናችንም ፡ ፊት ፡ እነዚያን ፡ ታላላቅ ፡ ተአምራት ፡ ያደረገ ፥ በሄድንበትም ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ ባለፍንባቸውም ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ የጠበቀን ፥ እርሱ ፡ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ነውና ። ፲፰፤ እግዚአብሔር ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፥ በምድሪቱም ፡ የተቀመጡትን ፡ አሞራውያን ፡ ከፊታችን ፡ አሳደደ ፤ ስለዚህ ፡ እርሱ ፡ አምላካችን ፡ ነውና ፡ እግዚአብሔርን ፡ እናመልካለን ።

፲፱፤ ኢያሱም ፡ ሕዝቡን ፦ እርሱ ፡ ቅዱስ ፡ አምላክ ፡ ነውና ፥ እርሱም ፡ ቀናተኛ ፡ አምላክ ፡ ነውና ፡ እግዚአብሔርን ፡ ማምለክ ፡ አትችሉም ፤ መተላለፋችሁንና ፡ ኃጢአታችሁን ፡ ይቅር ፡ አይልም ። ፳፤ እግዚአብሔርን ፡ ትታችሁ ፡ እንግዶችን ፡ አማልክት ፡ ብታመልኩ ፥ መልካም ፡ ካደረገላችሁ ፡ በኋላ ፡ ተመልሶ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ያደርግባችኋል ፥ ያጠፋችሁማል ፡ አላቸው ። ፳፩፤ ሕዝቡም ፡ ኢያሱን ፦ እንዲህ ፡ አይሁን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እናመልካለን ፡ አሉት ። ፳፪፤ ኢያሱም ፡ ሕዝቡን ፦ እንድታመልኩት ፡ እናንተ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንደ ፡ መረጣችሁ ፡ በራሳችሁ ፡ ላይ ፡ ምስክሮች ፡ ናችሁ ፡ አላቸው ፤ እነርሱም ፦ ምስክሮች ፡ ነን ፡ አሉ ። ፳፫፤ እርሱም ፦ አሁን ፡ እንግዲህ ፡ በመካከላችሁ ፡ ያሉትን ፡ እንግዶች ፡ አማልክት ፡ አርቁ ፥ ልባችሁንም ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ አምላክ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አዘንብሉ ፡ አላቸው ። ፳፬፤ ሕዝቡም ፡ ኢያሱን ፦ አምላካችንን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እናመልካለን ፥ ድምፁንም ፡ እንሰማለን ፡ አሉት ።

፳፭፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ኢያሱ ፡ ከሕዝቡ ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረገ ፥ በሴኬምም ፡ ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ አደረገላቸው ። ፳፮፤ ኢያሱም ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ ጻፈ ፤ ታላቁንም ፡ ድንጋይ ፡ ወስዶ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ አጠገብ ፡ ከነበረችው ፡ ከአድባሩ ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ አቆመው ። ፳፯፤ ኢያሱም ፡ ለሕዝቡ ፦ እነሆ ፥ የተናገረንን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ሰምቶአልና ፡ ይህ ፡ ድንጋይ ፡ ይመስክርብናል ፤ እንግዲህ ፡ አምላካችሁን ፡ እንዳትክዱ ፡ ይህ ፡ ምስክር ፡ ይሆንባችኋል ፡ አላቸው ። ፳፰፤ ኢያሱም ፡ ሕዝቡን ፡ በእያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ርስቱ ፡ ሰደደ ።

፳፱፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፡ ከዚህ ፡ ነገር ፡ በኋላ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡ የነዌ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡ ዕድሜው ፡ መቶ ፡ አሥር ፡ ዓመት ፡ ሲሆነው ፡ ሞተ ። ፴፤ በተራራማውም ፡ በኤፍሬም ፡ አገር ፡ በገዓስ ፡ ተራራ ፡ በሰሜን ፡ ባለችው ፡ በርስቱ ፡ ዳርቻ ፡ በተምናሴራ ፡ ቀበሩት ። ፴፩፤ ኢያሱ ፡ ባለበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፥ ከኢያሱም ፡ በኋላ ፡ በነበሩት ፡ ለእስራኤልም ፡ ያደረገውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ባወቁት ፡ በሽማግሌዎች ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፥ እስራኤል ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመለኩ ።

፴፪፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከግብፅ ፡ ያወጡትን ፡ የዮሴፍን ፡ አጥንት ፡ ያዕቆብ ፡ ከሴኬም ፡ አባት ፡ ከኤሞር ፡ ልጆች ፡ በመቶ ፡ በግ ፡ በገዛው ፡ እርሻ ፡ በሴኬም ፡ ቀበሩት ፤ እርሻውም ፡ ለዮሴፍ ፡ ልጆች ፡ ርስት ፡ ሆነ ። ፴፫፤ የአሮንም ፡ ልጅ ፡ አልዓዛር ፡ ሞተ ፤ በተራራማውም ፡ በኤፍሬም ፡ አገር ፡ ለልጁ ፡ ለፊንሐስ ፡ በተሰጠችው ፡ በጊብዓ ፡ መሬት ፡ ቀበሩት ።

# መ ጽ ሐ ፈ ፡ መ ሳ ፍ ን ት ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ኢያሱ ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፦ ከነዓናውያንን ፡ ለመውጋት ፡ ማን ፡ በፊት ፡ ይወጣልናል ? ብለው ፡ ፪፤ እግዚአብሔርን ፡ ጠየቁ ። እግዚአብሔርም ፦ ይሁዳ ፡ ይውጣ ፤ እነሆ ፥ ምድሪቱን ፡ በእጁ ፡ ፫፤ አሳልፌ ፡ ሰጥቻለሁ ፡ አለ ። ይሁዳም ፡ ወንድሙን ፡ ስምዖንን ፦ ከነዓናውያንን ፡ እንወጋ ፡ ዘንድ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ዕጣዬ ፡ ውጣ ፥ እኔም ፡ ደግሞ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ዕጣህ ፡ እሄዳለሁ ፡ አለው ። ስምዖንም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሄደ ። ፬፤ ይሁዳም ፡ ወጣ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ከነዓናውያንንና ፡ ፌርዛውያንን ፡ በእጃቸው ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፥ ከእነርሱም ፡ በቤዜቅ ፡ ውስጥ ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ገደሉ ። ፭፤ አዶኒቤዜቅንም ፡ በቤዜቅ ፡ አገኙትና ፡ ተዋጉት ፤ ከነዓናውያንንና ፡ ፌርዛውያንንም ፡ መቱአቸው ። ፮፤ አዶኒቤዜቅም ፡ ሸሸ ፤ አሳድደውም ፡ ያዙት ፥ የእጁንና ፡ የእግሩንም ፡ አውራ ፡ ጣት ፡ ቈረጡ ።

፯ አዶኒቤዜቅም ፡— የእጃቸውና ፡ የእግራቸው ፡ አውራ ፡ ጣት ፡ የተቈረጠ ፡ ሰባ ፡ ነገሥታት ፡ ከገበታዬ ፡ በታች ፡ ፍርፋሪ ፡ ይለቅሙ ፡ ነበር ፤ እኔ ፡ እንዳደረግሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲሁ ፡ መለሰልኝ ፡ አለ ። ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ አመጡት ÷ በዚያም ፡ ሞተ ።

፰ የይሁዳም ፡ ልጆች ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ተዋግተው ፡ ያዙአት ÷ በሰይፍ ፡ ስለትም ፡ መቱአት ÷ ከተማይቱንም ፡ በእሳት ፡ አቃጠሉአት ። ፱ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የይሁዳ ፡ ልጆች ፡ በተራራማው ፡ አገርና ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ በቈላውም ፡ ውስጥ ፡ የሚኖሩትን ፡ ከነዓናውያንን ፡ ሊወጉ ፡ ወረዱ ። ፲ ይሁዳም ፡ በኬብሮን ፡ የሚኖሩትን ፡ ከነዓናውያንን ፡ ሊወጋ ፡ ሄደ ። የኬብሮንም ፡ ስም ፡ አስቀድሞ ፡ ቂርያትአርባቅ ፡ ነበረ ። ሴሲንና ፡ አኪመንን ፡ ተላሚንም ፡ ገደሉ ።

፲፩ ከዚያም ፡ የዳቤርን ፡ ሰዎች ፡ ሊወጋ ፡ ሄደ ፤ አስቀድሞም ፡ የዳቤር ፡ ስም ፡ ቂርያትሤፍር ፡ ነበረ ። ፲፪ ካሌብም ፡— ቂርያትሤፍርን ፡ ለሚመታና ፡ ለሚይዝ ፡ ልጄን ፡ ዓክሳን ፡ አጋባዋለሁ ፡ አለ ። ፲፫ የካሌብም ፡ ትንሽ ፡ ወንድም ፡ የቄኔዝ ፡ ልጅ ፡ ጎቶንያል ፡ ያዛት ፤ ልጁንም ፡ ዓክሳን ፡ አጋባው ። ፲፬ እርስዋም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ በመጣች ፡ ጊዜ ፡ ከአበትዋ ፡ እርሻ ፡ እንዲለምን ፡ መከረችው ። እርስዋም ፡ ከአህያዋ ፡ ወረደች ፤ ካሌብም ፡— ምን ፡ ፈለግሽ ? አላት ። ፲፭ እርስዋም ፡— በረከትን ፡ ስጠኝ ፤ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ያለውን ፡ ምድር ፡ ሰጥተኸኛልና ፡ የውኃ ፡ ምንጭ ፡ ደግሞ ፡ ስጠኝ ፡ አለችው ። ካሌብም ፡ ላይኛውንና ፡ ታችኛውን ፡ ምንጭ ፡ ሰጣት ።

፲፮ የቄናዊው ፡ የሙሴ ፡ አማት ፡ ልጆችም ፡ ከይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ ዘንባባ ፡ ካለባት ፡ ከተማ ፡ ተነሥተው ፡ ከዓራድ ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወጡ ፤ ሄደውም ፡ ከሕዝቡ ፡ ጋር ፡ ተቀመጡ ። ፲፯ ይሁዳም ፡ ከወንድሙ ፡ ከስምዖን ፡ ጋር ፡ ሄደ ÷ በጽፋት ፡ የተቀመጡትንም ፡ ከነዓናውያንን ፡ መቱ ÷ ፈጽመውም ፡ አጠፉአት ። የከተማይቱንም ፡ ስም ፡ ሔርማ ፡ ብለው ፡ ጠሩአት ። ፲፰ ይሁዳም ፡ ጋዛንና ፡ ዳርቻዋን ÷ አስቀሎናንና ፡ ዳርቻዋን ÷ አቃሮንንና ፡ ዳርቻዋን ፡ ያዘ ። ፲፱ እግዚአብሔርም ፡ ከይሁዳ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፤ ይሁዳም ፡ ተራራማውን ፡ አገር ፡ ወረሰ ፤ በሸለቆው ፡ የሚኖሩት ፡ ግን ፡ የብረት ፡ ሰረገሎች ፡ ነበሩአቸውና ፡ ሊያወጣቸው ፡ አልቻለም ። ፳ ሙሴም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ለካሌብ ፡ ኬብሮንን ፡ ሰጡት ፤ ከዚያም ፡ ሦስቱን ፡ የዔናቅ ፡ ልጆች ፡ አወጣ ። ፳፩ ነገር ፡ ግን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩትን ፡ ኢያቡሳውያንን ፡ የብንያም ፡ ልጆች ፡ አላወጡአቸውም ፤ ኢያቡሳውያንም ፡ ከብንያም ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተቀምጠዋል ።

፳፪ የዮሴፍም ፡ ወገን ፡ ደግሞ ፡ በቤቴል ፡ ላይ ፡ ወጡ ÷ እግዚአብሔርም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረ ። ፳፫ የዮሴፍም ፡ ወገን ፡ ቤቴልን ፡ የሚሰልሉ ፡ ላኩ ። አስቀድሞም ፡ የከተማይቱ ፡ ስም ፡ ሎዛ ፡ ይባል ፡ ነበር ። ፳፬ ጠባቂዎቹም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ከከተማ ፡ ሲወጣ ፡ አይተው ፡— የከተማይቱን ፡ መግቢያ ፡ አሳየን ÷ እኛም ፡ ቸርነት ፡ እናደርግልሃለን ፡ አሉት ። ፳፭ የከተማይቱንም ፡ መግቢያ ፡ አሳያቸው ÷ ከተማይቱንም ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ መቱ ፤ ያንን ፡ ሰውና ፡ ወገኖቹን ፡ ግን ፡ ለቀቁአቸው ። ፳፮ ሰውዮውም ፡ ወደ ፡ ኬጢያውያን ፡ ምድር ፡ ሄደ ÷ በዚያም ፡ ከተማን ፡ ሠራ ÷ ስምዋንም ፡ ሎዛ ፡ ብሎ ፡ ጠራት ። እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ ስምዋ ፡ ይህ ፡ ነው ።

፳፯ ምናሴም ፡ የቤትሳንንና ፡ የመንደሮችዋን ÷ የታዕናክንና ፡ የመንደሮችዋን ÷ የዶርንና ፡ የመንደሮችዋን ÷ የይብለዓምንና ፡ የመንደሮችዋን ÷ የመጊዶንና ፡ የመንደሮችዋን ፡ ሰዎች ፡ አላወጣቸውም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከነዓናውያን ፡ በዚያ ፡ አገር ፡ በመቀመጥ ፡ ጸኑ ። ፳፰ እስራኤልም ፡ በበረቱ ፡ ጊዜ ፡ ከነዓናውያንን ፡ አስገበሩአቸው ÷ ፈጽመውም ፡ አላወጡአቸውም ።

፳፱ ኤፍሬምም ፡ በጌዝር ፡ የተቀመጡትን ፡ ከነዓናውያንን ፡ አላወጣቸውም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከነዓናውያን ፡ በመካከላቸው ፡ በጌዝር ፡ ተቀመጡ ።

፴ ዛብሎንም ፡ የቂድሮንንና ፡ የነህሎልን ፡ ሰዎች ፡ አላወጣቸውም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከነዓናውያን ፡ በመካከላቸው ፡ ተቀመጡ ÷ ግብርም ፡ የሚገብሩለት ፡ ሆኑ ።

፴፩ አሴርም ፡ የዓኮንና ፡ የሲዶንን ፡ የአሕላብንም ፡ የአክዚብንም ፡ የሒልባንም ፡ የአፌቅንም ፡ የረአብንም ፡ ሰዎች ፡ አላወጣቸውም ። ፴፪ በዚያችም ፡ ምድር ፡ የተቀመጡትን ፡ ከነዓናውያን ፡ አላወጡአቸውምና ፡ በመካከላቸው ፡ የአሴር ፡ ልጆች ፡ ተቀመጡ ።

፴፫ ንፍታሌምም ፡ የቤትሳሚስንና ፡ የቤትዓናትን ፡ ሰዎች ፡ አላወጣቸውም ÷ በምድሩም ፡ በተቀመጡት ፡ በከነዓናውያን ፡ መካከል ፡ ተቀመጡ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የቤትሳሚስና ፡ የቤትዓናት ፡ ሰዎች ፡ ግብር ፡ የሚገብሩለት ፡ ሆኑ ።

፴፬ አሞራውያንም ፡ የዳንን ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ተራራማው ፡ አገር ፡ እንዲያፈገፍጉ ፡ አስገደዱአቸው ÷ ወደ ፡ ሸለቆውም ፡ እንዳይወርዱ ፡ ከለከሉአቸው ። ፴፭ አሞራውያን ፡ በሔሬስ ፡ ተራራና ፡ በኤሎን ፡ በሸዓልቢምም ፡ በመቀመጥ ፡ ጸኑ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የዮሴፍ ፡ ቤት ፡ እጅ ፡ ከበደች ÷ አስገበረቻቸውም ። ፴፮ የአሞራውያንም ፡ ድንበር ፡ ከአቅረቢም ፡ ዐቀበት ፡ ከጭንጫው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ላይ ፡ ድረስ ፡ ነበረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ከጌልገላ ፡ ወደ ፡ በኪም ፡ ወጥቶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— እኔ ፡ ከግብፅ ፡ አውጥቻችኋለሁ ÷ ለአባቶቻችሁም ፡ ወደ ፡ ማልሁላቸው ፡ ምድር ፡ አግብቻችኋለሁ ፤ እኔም ፡— ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ያደረግሁትን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ለዘላለም ፡ አላፈርስም ፤ ፪ እናንተም ፡ መሠዊያ

ቸውን ፡ አፍርሱ ፡ እንጂ ፡ በዚህች ፡ ምድር ፡ ከሚ
ኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አታድርጉ ፡
አልሁ ። እናንተ ፡ ግን ፡ ቃሌን ፡ አልሰማች
፫ ሁም ፤ ይህንስ ፡ ለምን ፡ አደረጋችሁ ? ስለዚ
ህም ፡— ከፊታችሁ ፡ አላወጣቸውም ÷ ነገር ፡
ግን ፡ ያስጨንቋችኋል ÷ አማልክቶቻቸውም ፡
፬ ወጥመድ ፡ ይሆኑባችኋል ፡ አልሁ ። የእግዚአ
ብሔርም ፡ መልአክ ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ለእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ሁሉ ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡ ፡ ድም
፭ ፃቸውን ፡ እንሥተው ፡ አለቀሱ ። የዚያንም ፡
ስፍራ ፡ ስም ፡ ቦኪም ፡ ብለው ፡ ጠሩት ፤ በዚ
ያም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሠዉ ።

፮ ኢያሱም ፡ ሕዝቡን ፡ ባሰናበተ ፡ ጊዜ ፡ የእስ
ራኤል ፡ ልጆች ፡ ምድሪቱን ፡ ሊወርሱ ፡ ወደ ፡
፯ እየርስታቸው ፡ ሄዱ ። ኢያሱም ፡ በነበረበት ፡
ዘመን ፡ ሁሉ ÷ ለእስራኤልም ፡ ያደረገውን ፡ ታላ
ቁን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ በዩት ÷
ከኢያሱ ፡ በኋላ ፡ በነበሩ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ዘመን ፡
ሁሉ ÷ ሕዝቡ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመለኩ ።
፰ የእግዚአብሔርም ፡ ባሪያ ፡ የነዌ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡
ዕድሜው ፡ መቶ ፡ አሥር ፡ ዓመት ፡ ሲሆነው ፡
፱ ሞተ ። በተራራማውም ፡ በኤፍሬም ፡ አገር ፡
በገዓስ ፡ ተራራ ፡ በሰሜን ፡ ባለችው ፡ በርስቱ ፡
፲ ዳርቻ ፡ በተምናሔሬስ ፡ ቀበሩት ። ትውልድ ፡
ሁሉ ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ አባቶቻቸው ፡ ተከማቹ ፤
ከእነዚያም ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለእስራኤ
ልም ፡ ያደረገውን ፡ ሥራ ፡ ያላወቀ ፡ ሌላ ፡ ትው
ልድ ፡ ተነሣ ።

፲፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ክፉ ፡ የሆነ ፡ ነገር ፡ አደረጉ ÷ በአሊ
፲፪ ምንም ፡ አመለኩ ። ከግብፅ ፡ ምድርም ፡ ያወ
ጣቸውን ፡ የአባቶቻቸውን ፡ አምላክ ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ ተዉ ÷ በዙሪያቸውም ፡ ካሉት ፡
ከአሕዛብ ፡ አማልክት ፡ ሌሎችን ፡ አማልክት ፡
ተከተሉ ÷ ሰገዱላቸውም ፤ እግዚአብሔርንም ፡
፲፫ አስቈጡ ። እግዚአብሔርንም ፡ ትተው ፡ በአ
፲፬ ልንና ፡ አስታሮትን ፡ አመለኩ ። የእግዚአብ
ሔርም ፡ ቍጣ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ነደደ ÷ ወደ ፡
ማረኩአቸውም ፡ ማራኪዎች ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡
ሰጣቸው ፤ በዙሪያቸውም ፡ ባሉት ፡ በጠላቶቻ
ቸው ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ÷ ጠላቶቻቸ
ውንም ፡ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ሊቋቋሙ ፡ አልቻ
፲፭ ሉም ። እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ÷
እግዚአብሔርም ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ማለ ÷
ወደ ፡ ወጡበት ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡
ትከፋባቸው ፡ ነበረች ፤ እጅግም ፡ ተጨነቁ ።

፲፮ እግዚአብሔርም ፡ መሳፍንትን ፡ አስነሣላ
ቸው ÷ ከሚማርኩአቸውም ፡ እጅ ፡ አዳኑአ
፲፯ ቸው ። ሌሎች ፡ አማልክትን ፡ ተከትለው ፡ አመነ
ዘሩ ፡ ሰገዱላቸውም ፡ እንጂ ፡ መሳፍንቶቻቸ
ውን ፡ አልሰሙም ፤ አባቶቻቸውም ፡ ይሄዱበት ፡
ከነበረ ፡ መንገድ ፡ ፈጥነው ፡ ፈቀቅ ፡ አሉ ፤ አባ
ቶቻቸው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ እንደ ፡
፲፰ ታዘዙ ፡ እንዲሁ ፡ አላደረጉም ። እግዚአብሔ
ርም ፡ መሳፍንትን ፡ ባስነሣላቸው ፡ ጊዜ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ከመስፍኑ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፤ እግዚአ
ብሔርም ፡ ስለሚጋፉአቸውና ፡ ስለሚያስጨን
ቋቸው ፡ በጭንቀታቸው ፡ ያዝን ፡ ነበርና ፡ በመ
ስፍኑ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ከጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡
፲፱ አዳናቸው ። መስፍኑ ፡ ግን ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡
ይመለሱ ፡ ነበር ÷ ሌሎችንም ፡ አማልክት ፡
በመከተላቸው ፡ እነርሱንም ፡ በማምለካቸውና ፡
ለእነርሱ ፡ በመስገዳቸው ፡ አባቶቻቸው ፡ አድ
ርገውት ፡ ከነበረው ፡ የከፋ ፡ ያደርጉ ፡ ነበር ፤
የእልከኝነታቸውን ፡ መንገድና ፡ ሥራቸውን ፡
፳ አልተዉም ፡ ነበር ። የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ነደደ ÷ እንዲህም ፡ አለ ፡—
ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ለአባቶቻቸው ፡ ያዘዝሁትን ፡ ቃል ፡
ኪዳን ፡ ስለ ፡ ተላለፉ ÷ ድምፄንም ፡ ስላልሰሙ ፡
፳፩፡፳፪ አባቶቻቸውም ፡ እንደ ፡ ጠበቁ ÷ ይሄዱበት ፡
ዘንድ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንገድ ፡ ይጠብቁ ፡
ወይም ፡ አይጠብቁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እስራኤልን ፡
እፈትንባቸው ፡ ዘንድ ÷ ኢያሱ ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡
ከተዋቸው ፡ አሕዛብ ፡ አንዱን ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡
ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ከፊታቸው ፡ አላወጣም ።
፳፫ እግዚአብሔርም ፡ እነዚህን ፡ አሕዛብ ፡ አስቀረ ÷
ፈጥኖም ፡ አላወጣቸውም ÷ በኢያሱም ፡ እጅ ፡
አሳልፎ ፡ አልሰጣቸውም ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፡፪ ከከነዓናውያንም ፡ ጋር ፡ መዋጋት ፡ ያላወቁ
ትን ፡ እስራኤልን ፡ በእነርሱ ፡ ይፈትናቸው ፡
ዘንድ ÷ በፊትም ፡ ሰልፍን ፡ ያልለመዱ ፡ የእስ
ራኤል ፡ ልጆች ፡ ትውልድ ፡ መዋጋትን ፡ ያው
ቁና ፡ ይማሩ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያስቀራ
፫ ቸው ፡ አሕዛብ ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ አምስቱ ፡ የፍ
ልስጥኤማውያን ፡ መኳንንት ÷ ከነዓናውያንም ፡
ሁሉ ÷ ሲዶናውያንም ÷ ከበኣልአርሞንዔም ፡
ተራራ ፡ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሐማት ፡ መግቢያ ፡ ድረስ ፡
በሊባኖስ ፡ ተራራ ፡ የሚኖሩትም ፡ ኤዊያውያን ።
፬ እግዚአብሔር ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ ለአባቶቻቸው ፡
ያዘዘውን ፡ ትእዛዝ ፡ መስማታቸው ፡ እንዲታ
ወቅ ፡ እስራኤል ፡ ይፈተኑባቸው ፡ ዘንድ ፡ እነዚህ ፡
፭ ቀሩ ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በከነዓናውያን ፡
በኬጢያውያንም ፡ በአሞራውያንም ፡ በፌርዛ
ውያንም ፡ በኤዊያውያንም ፡ በኢያቡሳውያንም ፡
፮ መካከል ፡ ተቀመጡ ። ሴት ፡ ልጆቻቸውንም ፡
አገቡአቸው ÷ እነርሱም ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸ
ውን ፡ ለወንዶች ፡ ልጆቻቸው ፡ ሰጡ ÷ አማል
ክቶቻቸውንም ፡ አመለኩ ።

፯ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ክፉ ፡ የሆነውን ፡ ነገር ፡ አደረጉ ÷ አምላካ
ቸውንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ረስተው ፡ በአሊም
፰ ንና ፡ አስታሮትን ፡ አመለኩ ። ስለዚህ ፡ የእግዚአ
ብሔር ፡ ቍጣ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ነደደ ÷ በመ
ስጴጦምያ ፡ ንጉሥ ፡ በኵሰርሰቴም ፡ እጅ ፡ አሳ
ልፎ ፡ ሰጣቸው ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ለኵሰ
፱ ርሰቴም ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡ ተገዙለት ። የእስራ

ኤልም ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ፤
እግዚአብሔርም ፡ የሚያድናቸውን ፡ አዳኝ ፡
የካሌብን ፡ የታናሽ ፡ ወንድሙን ፡ የቄኔዝን ፡
፲ ልጅ ፡ ጎቶንያልን ፡ አስነሣላቸው ። የእግዚአ
ብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ መጣ ÷
በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ይፈርድ ፡ ነበር ፤ ለሰልፍ ፡
ወጣ ÷ እግዚአብሔርም ፡ የመስጴጦምያን ፡
ንጉሥ ፡ ኵሰርሰቴምን ፡ በእጁ ፡ አሳልፎ ፡
ሰጠው ፤ እጁም ፡ በኵሰርሰቴም ፡ ላይ ፡ አሸነ
፲፩ ፈች ። ምድሪቱም ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ዐረፈች ፤
የቄኔዝም ፡ ልጅ ፡ ጎቶንያል ፡ ሞተ ።
፲፪ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ሠሩ ፤ በእግዚ
አብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ስለ ፡ ሠሩ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ የሞዓብን ፡ ንጉሥ ፡ ዔግሎምን ፡ በእስራ
፲፫ ኤል ፡ ላይ ፡ አበረታባቸው ። የአሞንን ፡ ልጆ
ችና ፡ አማሌቅን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ሰበሰበ ፤ ሄዶም ፡
እስራኤልን ፡ መታ ÷ ዘንባባም ፡ ያለባትን ፡ ከተማ ፡
፲፬ ያዙአት ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ለሞዓብ ፡
ንጉሥ ፡ ለዔግሎም ፡ አሥራ ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡
ተገዙለት ።
፲፭ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ጮኹ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ብንያማዊውን ፡ የጌ
ራን ፡ ልጅ ፡ ናዖድን ፡ ግራኙን ፡ ሰው ፡ አዳኝ ፡
አስነሣላቸው ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በእ
ርሱ ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ ሞዓብ ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ዔግ
፲፮ ሎም ፡ ግብር ፡ ላኩ ። ናዖድም ፡ ሁለት ፡ አፍ ፡
ያለው ፡ ርዝመቱ ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፡ ሰይፍ ፡
አበጀ ÷ ከልብሱም ፡ በታች ፡ በቀኝ ፡ ጭኑ ፡
፲፯ በኩል ፡ አደረገው ። ለሞዓብም ፡ ንጉሥ ፡ ለዔ
ግሎም ፡ ግብሩን ፡ አቀረበ ፤ ዔግሎምም ፡ እጅግ ፡
፲፰ ወፍራም ፡ ሰው ፡ ነበረ ። ግብሩንም ፡ ማቅረብ ፡
በጨረሰ ፡ ጊዜ ÷ ግብር ፡ የተሸከሙትን ፡ ሰዎች ፡
፲፱ ሰደደ ። ናዖድ ፡ ግን ፡ በጌልገላ ፡ ከነበሩት ፡
ትክል ፡ ድንጋዮች ፡ ዘንድ ፡ ተመልሶ ፡— ንጉሥ ፡
ሆይ ÷ የምሥጢር ፡ ነገር ፡ አለኝ ፡ አለ ፤ ንጉ
ሡም ፡— ዝም ፡ በል ፡ አለ ፤ በዙሪያውም ፡ የቆሙት ፡
፳ ሁሉ ፡ ወጡ ። ናዖድም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀረበ ፤
እርሱም ፡ በሰገነት ፡ ቤት ፡ ለብቻው ፡ ተቀምጦ ፡
ነበር ። ናዖድም ፡— የእግዚአብሔር ፡ መልእክት ፡
ለአንተ ፡ አለኝ ፡ አለ ። ከዙፋኑም ፡ ተነሣ ።
፳፩ ናዖድም ፡ ግራ ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡ ከቀኝ ፡ ጭኑ ፡
፳፪ ሰይፉን ፡ ወሰደ ÷ ሆዱንም ፡ ወጋው ፤ የሰይፉም ፡
እጀታው ፡ ደግሞ ፡ ከስለቱ ፡ በኋላ ፡ ገባ ፤ ስቡም ፡
ስለቱን ፡ ከደነው ÷ ሰይፉንም ፡ ከሆዱ ፡ መልሶ ፡
፳፫ አላወጣውም ፤ በኋላውም ፡ ወጣ ። ናዖድም ፡
ወደ ፡ ደርቡ ፡ ወጣ ÷ የሰገነቱንም ፡ ደጅ ፡ ዘግቶ ፡
ቈለፈው ።
፳፬ ናዖድም ፡ ከሄደ ፡ በኋላ ፡ በሪያዎቹ ፡ መጡ ፤
የሰገነቱም ፡ ደጅ ፡ ተቈልፎ ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡—
ምናልባት ፡ በሰገነቱ ፡ ውስጥ ፡ ወገቡን ፡ ይሞ
፳፭ ክር ፡ ይሆናል ፡ አሉ ። እስኪያፍሩም ፡ ድረስ ፡
እጅግ ፡ ዘገዩ ፤ የሰገነቱንም ፡ ደጅ ፡ እንዳልከ
ፈተ ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ መክፈቻውን ፡ ወስደው ፡
ከፈቱ ÷ እነሆም ÷ ጌታቸው ፡ በምድር ፡ ወድቆ ፡
ሞቶም ፡ አገኙት ።
፳፮ በዘገዩበትም ፡ ጊዜያት ፡ ናዖድ ፡ ሸሸ ÷ ትክል ፡
ድንጋዮቹንም ፡ አለፈ ÷ ወደ ፡ ሴይሮታም ፡ አመ
፳፯ ለጠ ። በመጣም ፡ ጊዜ ፡ በተራራማው ፡ በኤፍ
ሬም ፡ አገር ፡ ቀንደ ፡ መለከት ፡ ነፋ ፤ የእስራኤ
ልም ፡ ልጆች ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ከተራራማው ፡
አገር ፡ ወረዱ ÷ እርሱም ፡ በፊታቸው ፡ ሄደ ።
፳፰ እርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡ ጠላቶቻችሁን ፡
ሞዓባውያንን ፡ በእጃችሁ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶአ
ልና ፡ ተከተሉኝ ፡ አላቸው ። ተከትለውትም ፡
ወረዱ ÷ ወደ ፡ ሞዓብም ፡ የሚያሻግረውን ፡ የዮ
ርዳኖስን ፡ መሻገርያ ፡ ያዙ ÷ ማንንም ፡ አላሳለ
፳፱ ፉም ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ከሞዓብ ፡ አሥር ፡
ሺህ ፡ የሚያህሉትን ÷ ጕልማሶችና ፡ ጽኑዓን ፡
ሁሉ ÷ መቱ ፤ አንድ ፡ እንኳ ፡ አላመለጠም ።
፴ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሞዓብ ፡ ከእስራኤል ፡ እጅ ፡
በታች ፡ ተዋረደ ፤ ምድሪቱም ፡ ሰማንያ ፡ ዓመት ፡
ዐረፈች ።
፴፩ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ የዓናት ፡ ልጅ ፡ ሰሜጋር ፡
ተነሣ ÷ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡
ሰው ፡ በበሬ ፡ መውጊያ ፡ ገደለ ፤ እርሱም ፡
ደግሞ ፡ እስራኤልን ፡ አዳነ ።

ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ናዖድም ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡
፪ ሠሩ ። እግዚአብሔርም ፡ በአሶር ፡ በነገሠው ፡
በከነዓን ፡ ንጉሥ ፡ በኢያቢስ ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡
ሰጣቸው ፤ የሠራዊቱም ፡ አለቃ ፡ በአሕዛብ ፡
፫ አሪሶት ፡ የተቀመጠው ፡ሲሣራ ፡ ነበረ ። የእስ
ራኤልም ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ፤
ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ የብረት ፡ ሰረገሎች ፡ ነበሩትና ÷
የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ ሀያ ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡
እጅግ ፡ ያስጨንቃቸው ፡ ነበር ።
፬ በዚያ ፡ ጊዜም ፡ ነቢይቱ ፡ የለፊዶት ፡ ሚስት ፡
ዲቦራ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ትፈርድ ፡ ነበረች ።
፭ እርስዋም ፡ በተራራማው ፡ በኤፍሬም ፡ አገር ፡
በራማና ፡ በቤቴል ፡ መካከል ፡ ካለው ፡ የዲቦራ ፡
ዛፍ ፡ ከሚባለው ፡ ከዘንባባው ፡ በታች ፡ ተቀ
ምጣ ፡ ነበር ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ እር
፮ ስዋ ፡ ለፍርድ ፡ ይወጡ ፡ ነበር ። ልካም ፡ ከቃ
ዴስ ፡ ንፍታሌም ፡ የአቢኒኤምን ፡ ልጅ ፡ ባር
ቅን ፡ ጠርታ ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡— ሄደህ ፡ ወደ ፡ ታቦር ፡ ተራራ ፡ ውጣ ÷
ከአንተም ፡ ጋር ፡ ከንፍታሌምና ፡ ከዛብሎን ፡
፯ ልጆች ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ውሰድ ፤ እኔም ፡
የኢያቢስን ፡ ሠራዊት ፡ አለቃ ፡ ሲሣራን ፡ ሰረገ
ሎቹንም ፡ ሕዝቡንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ወደ ፡
ቂሶን ፡ ወንዝ ፡ እስባለሁ ÷ በእጅህም ፡ አሳልፌ ፡
እሰጠዋለሁ ፡ ብሎ ፡ አላዘዘህምን ? አለችው ።
፰ ባርቅም ፡— አንቺ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ብትሄጂ ፡ እኔ ፡
እሄዳለሁ ፤ አንቺ ፡ ግን ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ባትሄጂ ፡
፱ እኔ ፡ አልሄድም ፡ አላት ። እርስዋም ፡— በእው

ነት ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ እሄዳለሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሲሣራን ፡ በሴት ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣልና ፡ በዚህ ፡ በምትሄድበት ፡ መንገድ ፡ ለአንተ ፡ ክብር ፡ አይሆንም ፡ አለችው ። ዲቦራም ፡ ተነሥታ ፡ ከባርቅ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ቃዴስ ፡ ሄደች ። ፲ ባርቅም ፡ ዛብሎንንና ፡ ንፍታሌምን ፡ ወደ ፡ ቃዴስ ፡ ጠራቸው ፥ አሥር ፡ ሺህም ፡ ሰዎች ፡ ተከተለውት ፡ ወጡ ፤ ዲቦራም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ወጣች ።

፲፩ ቄናዊውም ፡ ሔቤር ፡ ከሙሴ ፡ አማት ፡ ከአባብ ፡ ልጆች ፡ ከቄናውያን ፡ ተለይቶ ፡ ድንኳኑን ፡ በቃዴስ ፡ አጠገብ ፡ በጻዕናይም ፡ እስከ ፡ ነበረው ፡ እስከ ፡ ትልቁ ፡ ዛፍ ፡ ድረስ ፡ ተከለ ።

፲፪ የአቢኒኤምም ፡ ልጅ ፡ ባርቅ ፡ ወደ ፡ ታቦር ፡ ተራራ ፡ እንደ ፡ ወጣ ፡ ለሲሣራ ፡ ነገሩት ። ፲፫ ሲሣራም ፡ ሰረገሎቹን ፡ ሁሉ ፥ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ የብረት ፡ ሰረገሎች ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩትን ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ከአረሶት ፡ ወደ ፡ ቂሶን ፡ ወንዝ ፡ ሰበሰባቸው ። ፲፬ ዲቦራም ፡ ባርቅን ፦ እግዚአብሔር ፡ ሲሣራን ፡ በእጅህ ፡ አሳልፎ ፡ የሚሰጥበት ፡ ቀን ፡ ዛሬ ፡ ነውና ፡ ተነሣ ፤ እነሆ ፥ እግዚአብሔር ፡ በፊትህ ፡ ወጥቶአል ፡ አለችው ። ባርቅም ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ተከትለውት ፡ ከታቦር ፡ ተራራ ፡ ወረደ ። ፲፭ እግዚአብሔርም ፡ ሲሣራን ፡ ሰረገሎቹንም ፡ ሁሉ ፡ ሠራዊቱንም ፡ ሁሉ ፡ ከባርቅ ፡ ፊት ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ አስደነገጣቸው ፤ ሲሣራም ፡ ከሰረገላው ፡ ወርዶ ፡ በእግሩ ፡ ሸሸ ። ፲፮ ባርቅም ፡ ሰረገሎችንና ፡ ሠራዊቱን ፡ እስከ ፡ አሪሶት ፡ ድረስ ፡ አባረረ ፤ የሲሣራም ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ ወደቀ ፤ አንድ ፡ እንኳ ፡ አልቀረም ።

፲፯ በአሶር ፡ ንጉሥም ፡ በኢያቢስና ፡ በቄናዊው ፡ በሔቤር ፡ ቤት ፡ መካከል ፡ ሰላም ፡ ነበረና ፡ ሲሣራ ፡ በእግሩ ፡ ሸሽቶ ፡ ወደ ፡ ቄናዊው ፡ ወደ ፡ ሔቤር ፡ ሚስት ፡ ወደ ፡ ኢያዔል ፡ ድንኳን ፡ ደረሰ ። ፲፰ ኢያዔልም ፡ ሲሣራን ፡ ለመገናኘት ፡ ወጥታ ፦ ግባ ፥ ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ እኔ ፡ ግባ ፤ አትፍራ ፡ አለችው ። ወደ ፡ እርስዋም ፡ ወደ ፡ ድንኳንዋ ፡ ገባ ፥ በመጐናጸፊያዋም ፡ ሸፈነችው ። ፲፱ እርሱም ፦ ጠምቶኛልና ፡ እባክሽ ፡ የምጠጣው ፡ ጥቂት ፡ ውኃ ፡ ስጭኝ ፡ አላት ፤ እርስዋም ፡ የወተቱን ፡ አቁማዳ ፡ ፈትታ ፡ አጠጣችው ፥ ሸፈነችውም ። ፳ እርሱም ፦ ከድንኳኑ ፡ ደጃፍ ፡ ቁሚ ፤ ሰውም ፡ መጥቶ ፦ በዚህ ፡ ሰው ፡ አለን? ብሎ ፡ ቢጠይቅሽ ፡ አንቺ ፦ የለም ፡ ትዪዋለሽ ፡ አላት ። ፳፩ የሔቤርም ፡ ሚስት ፡ ኢያዔል ፡ የድንኳን ፡ ካስማ ፡ ወሰደች ፥ በእጅዋም ፡ መዶሻ ፡ ያዘች ፥ ቀስ ፡ ብላም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀረበች ፤ በጆሮግንዱ ፡ ካስማውን ፡ ቸነከረች ፤ እርሱም ፡ ደክሞ ፡ አንቀላፍቶ ፡ ነበርና ፡ ካስማው ፡ ወደ ፡ መሬት ፡ ጠለቀ ፥ እርሱም ፡ ሞተ ። ፳፪ እነሆም ፥ ባርቅ ፡ ሲሣራን ፡ ሲያባርር ፡ ኢያዔል ፡ ልትገናኘው ፡ ወጥታ ፦ ና ፡ የምትሻውንም ፡ ሰው ፡ አሳይሃለሁ ፡ አለችው ። ወደ ፡ እርስዋም ፡ ገባ ፥ እነሆም ፥ ሲሣራ ፡ ወድቆ ፡ ሞቶም ፡ አገኘው ፥ ካስማውም ፡ ከጆሮግንዱ ፡ ውስጥ ፡ ነበረ ።

፳፫ በዚያም ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ የከነዓንን ፡ ንጉሥ ፡ ኢያቢስን ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ አዋረደ ። ፳፬ የከነዓንን ፡ ንጉሥ ፡ ኢያቢስንም ፡ እስኪያጠፉ ፡ ድረስ ፡ በከነዓን ፡ ንጉሥ ፡ በኢያቢስ ፡ ላይ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ እየበረታች ፡ ሄደች ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ በዚያም ፡ ቀን ፡ ዲቦራና ፡ የአቢኒኤም ፡ ልጅ ፡ ባርቅ ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ ተቀኙ ፦

፪ በእስራኤል ፡ ውስጥ ፡ መሪዎች ፡ ስለ ፡ መሩ ፥
ሕዝቡም ፡ ነፍሳቸውን ፡ በፈቃዳቸው ፡ ስለ ፡ ሰጡ ፥
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ።
፫ ነገሥታት ፡ ሆይ ፥ ስሙ ፤
መኳንንት ፡ ሆይ ፥ አድምጡ ፤
እኔ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እቀኛለሁ ፥
ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እዘምራለሁ ።
፬ አቤቱ ፥ ከሴይር ፡ በወጣህ ፡ ጊዜ ፥
ከኤዶምያስም ፡ ሜዳ ፡ በተራመድህ ፡ ጊዜ ፥
ምድሪቱ ፡ ተናወጠች ፥ ሰማያቱም ፡ አንጠበጠቡ ፤
ደመናትም ፡ ደግሞ ፡ ውኃን ፡ አንጠበጠቡ ።
፭ ተራሮች ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የተነሣ ፡ ቀለጡ ፥
ያም ፡ ሲና ፡ ከእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የተነሣ ።
፮ በዓናት ፡ ልጅ ፡ በሰሜጋር ፡ ዘመን ፥
በኢያዔል ፡ ዘመን ፡ መንገዶች ፡ ተቋረጡ ፤
መንገደኞች ፡ በስርጥ ፡ መንገድ ፡ ይሄዱ ፡ ነበር ።
፯ አንቺ ፥ ዲቦራ ፥ እስክትነሺ ፡ ድረስ ፥
ለእስራኤልም ፡ እናት ፡ ሆነሽ ፡ እስክትነሺ ፡ ድረስ ፥
ኃያላን ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ አነሱ ፥ አለቁም ።
፰ አዲሶች ፡ አማልክትን ፡ መረጡ ፤
በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ሰልፍ ፡ በበሮች ፡ ሆነ ፤
በአርባ ፡ ሺህ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ጦርና ፡ ጋሻ ፡ አልታየም ።
፱ ልቤ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ አለቆች ፡ ነው ፥
በሕዝቡ ፡ መካከል ፡ ነፍሳቸውን ፡ በፈቃዳቸው ፡ ወደ ፡ ሰጡት ፤
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ።
፲ በነጫጭ ፡ አህዮች ፡ ላይ ፡ የምትጫኑ ፥
በወላንሳ ፡ ላይ ፡ የምትቀመጡ ፥
በመንገድም ፡ የምትሄዱ ፥ ተናገሩ ።
፲፩ በማጠጫው ፡ መካከል ፡ ከሉት ፡ ከቀስተኞች ፡ ጩኸት ፡ ርቀው ፥
በዚያ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ጽድቅ ፥

በእስራኤል ፡ ላይ ፡ የግዛቱን ፡ ጽድቅ ፡
ይጫወታሉ ፤
ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡
ወደ ፡ በሮች ፡ ወረዱ ።
፲፪ ንቂ ÷ ንቂ ÷ ዲቦራ ፡ ሆይ ፤
ንቂ ÷ ንቂ ÷ ቅኔውን ፡ ተቀኚ ፤
ባርቅ ፡ ሆይ ÷ ተነሣ ፤
የአቢኒኤም ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ምርኮህን ፡
ማርክ ።
፲፫ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ የቀሩት ፡ ወደ ፡ ኃያላኑና ፡
ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ ወረዱ ፤
እግዚአብሔርም ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ በኃያላን ፡
ላይ ፡ ወረደ ።
፲፬ በአማሌቅ ፡ ዘንድ ፡ ሥር ፡ የነበራቸው ፡
እነርሱ ፡ ከኤፍሬም ÷
ብንያም ፡ ሆይ ÷ በሕዝብህ ፡ መካከል ፡
ከአንተ ፡ በኋላ ፡ ወረዱ ፤
አለቆች ፡ ከማኪር ÷ የንጉሥንም ፡ ዘንግ ፡
የሚይዙ ፡ ከዛብሎን ፡ ወረዱ ።
፲፭ የይሳኮርም ፡ አለቆች ፡ ከዲቦራ ፡ ጋር ፡
ነበሩ ፤
ይሳኮርም ፡ እንደ ፡ ባርቅ ፡ ነበረ ፤
ከእግሩ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሸለቆው ፡ ቸኰሉ ፤
በሮቤል ፡ ፈሳሾች ፡ አጠገብ ፡ ብዙ ፡ የልብ ፡
ማመንታት ፡ ነበረ ።
፲፮ መንጎች ፡ ሲያፍዋጩ ፡ ለመስማት ፡
በበጎች ፡ ጕረኖ ፡ መካከል ፡ ለምን ፡ ተቀ
መጥህ ?
በሮቤል ፡ ፈሳሾች ፡ አጠገብ ፡ ታላቅ ፡
የልብ ፡ ምርምር ፡ ነበረ ።
፲፯ ገለዓድ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ተቀመጠ ፤
ዳንም ፡ ለምን ፡ በመርከብ ፡ ውስጥ ፡ ቀረ ?
አሴርም ፡ በባሕሩ ፡ ዳር ፡ ተቀመጠ ÷
በወንዞቹም ፡ ዳርቻ ፡ ዐረፈ ።
፲፰ ዛብሎን ፡ ነፍሱን ፡ ወደ ፡ ሞት ፡ ያሳለፈ ፡
ሕዝብ ፡ ነው ÷
ንፍታሌምም ፡ በአገሩ ፡ ከረብታ ፡ ላይ ፡ ነው ።
፲፱ ነገሥታት ፡ መጡ ÷ ተዋጉም ፤
በዚያ ፡ ጊዜ ፡ በመጊዶ ፡ ውኆች ፡ አጠ
ገብ ፡ በታዕናክ ፡
የከነዓን ፡ ነገሥታት ፡ ተዋጉ ፤
የብር ፡ ዘረፋም ፡ አልወሰዱም ።
፳ ከዋክብት ፡ ከሰማይ ፡ ተዋጉ ፤
በአካሄዳቸውም ፡ ከሲሣራ ፡ ጋር ፡ ተዋጉ ።
፳፩ ከዱሮ ፡ ጀምሮ ፡ የታወቀ ፡ ያ ፡ የቂሶን ፡
ወንዝ ÷
የቂሶን ፡ ወንዝ ፡ ጠርጎ ፡ ወሰዳቸው ።
ነፍሴ ፡ ሆይ ÷ በኃይል ፡ እርገጪ ።
፳፪ ከኃያላን ፡ ግልቢያ ፡ ብርታት ፡ የተነሣ ፡
የፈረሶች ፡ ጥፍሮች ፡ ተቀጠቀጡ ።
፳፫ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ — ሜሮዝን ፡
እርገሙ ፤
እግዚአብሔርን ፡ በኃያላን ፡ መካከል ፡ ለመ
ርዳት ÷
እግዚአብሔርን ፡ ለመርዳት ፡ አልመጡ
ምና ፡
የተቀመጡባትን ፡ ሰዎች ፡ ፈጽማችሁ ፡
እርገሙ ፡ አለ ።
፳፬ የቄናዊው ፡ የሔቤር ፡ ሚስት ፡ ኢያዔል ፡
ከሴቶች ፡ ይልቅ ፡ የተባረከች ፡ ትሁን ፤
በድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ከሚኖሩ ፡ ሴቶች ፡
ይልቅ ፡ የተባረከች ፡ ትሁን ።
፳፭ ውኃ ለመነ ÷ ወተትም ፡ ሰጠችው ፤
በተከበረ ፡ ዳካ ፡ እርጎ ፡ አቀረበችለት ።
፳፮ እጅዋን ፡ ወደ ፡ ካስማ ÷
ቀኝ ፡ እጅዋንም ፡ ወደ ፡ ሠራተኛ ፡ መዶሻ ፡
አደረገች ፤
በመዶሻውም ፡ ሲሣራን ፡ መታች ÷ ራሱ
ንም ፡ ቸነከረች ፤
ጆሮግንዱንም ፡ በሳች ÷ ጎዳችውም ።
፳፯ በእግሮችዋ ፡ አጠገብ ፡ ተደፋ ÷ ወደቀ ÷
ተኛ ፤
በእግሮችዋ ፡ አጠገብ ፡ ተደፋ ÷ ወደቀ ፤
በተደፋበት ፡ ስፍራ ፡ በዚያ ፡ ወድቆ ፡ ሞተ ።
፳፰ ከመስኮት ፡ ሆና ፡ ተመለከተች ፤
የሲሣራ ፡ እናት ፡ በሰቅሰቅ ፡ ዘልቃ ፡ —
ስለ ፡ ምን ፡ ለመምጣት ፡ ሰረገላው ፡ ዘገየ ?
ስለ ፡ ምንስ ፡ የሰረገላው ፡ መንኰራኵር ፡
ቈየ ? ብላ ፡ ጮኸች ።
፳፱ ብልሃተኞች ፡ ሴቶችዋ ፡ መለሱላት ፤
እርስዋ ፡ ደግሞ ፡ ለራስዋ ፡ እንዲህ ፡ ብላ ፡
መለሰች ፡—
፴ ምርኮ ፡ አግኝተው ፡ የለምን ? ተካፍለ
ውስ ፡ የለምን ?
ለእያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ ምርኮ ፡ አንዲት ፡
ወይም ፡ ሁለት ፡ ቈነጃጅት ፤
ለሲሣራ ፡ ምርኮ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ያለው ፡
ልብስ ÷
በአንገትጌ ፡ ላይ ፡ በሁለት ፡ እጥፍ ፡ የተጠ
ለፈ ፡ ዝንጕርጕር ፡ ልብስ ።
፴፩ አቤቱ ÷ ጠላቶችህ ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ ይጥፉ ፤
ወዳጆችህ ፡ ግን ፡ ፀሐይ ፡ በኃይሉ ፡ በወጣ ፡
ጊዜ ፡ እንደሚሆን ÷ እንዲሁ ፡ ይሁኑ ።
ምድሪቱም ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ ዐረፈች ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ሠሩ ፤ እግዚአብሔርም ፡ በምድያም ፡ እጅ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ። ፪ የምድያምም ፡ እጅ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ጠነከረች ፤ ከምድያምም ፡ የተነሣ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ ጕድጓድና ፡ ዋሻ ፡ ምሽግም ፡ አበጁ ። ፫ እስራኤልም ፡ ዘር ፡ በዘሩ ፡ ጊዜ ፡ ምድያማውያን ፡ አማሌቃውያንም ፡ በምሥራቅም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ይመጡባቸው ፡ ነበር ፤ ፬ በእነርሱም ፡ ላይ ፡ ይሰፍሩ ፡ ነበር ÷ እስከ ፡ ጋዛም ፡ ድረስ ፡ የምድሩን ፡ ቡቃያ ፡ ያጠፉ ፡ ነበር ÷ ምግብንም ፡ ለእስራኤል ፡ አይ

ተዉም ፡ ነበር ፤ በግ ፡ ወይም ፡ በሬ ፡ ወይም ፡
፭፤ አህያ ፡ ቢሆን ፡ አይተዉም ። እንስሶቻቸውንና ፡
ድንኳኖቻቸውን ፡ ይዘው ፡ በብዛት ፡ እንደ ፡ አን
በጣ ፡ ሆነው ፡ ይመጡ ፡ ነበር ፤ ለእነርሱና ፡ ለግ
መሎቻቸውም ፡ ቍጥር ፡ አልነበራቸውም ፤
ምድሪቱንም ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ ይመጡ ፡ ነበር ።
፮፤ ከምድያምም ፡ የተነሣ ፡ እስራኤል ፡ እጅግ ፡
ተጠቁ ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ጮኹ ።

፯፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በምድ
ያም ፡ ምክንያት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ በጮኹ ፡
፰፤ ጊዜ ፥ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ልጆች ፡
ነቢይ ፡ ላከ ፥ እርሱም ፡ አለ ፡— የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እኔ ፡ ከግ
ብፅ ፡ ምድር ፡ አወጣኋችሁ ፥ ከባርነትም ፡ ቤት ፡
፱፤ አስለቀቅኋችሁ ፤ ከግብፃውያንም ፡ እጅ ፥ ከሚ
ጋፉአችሁም ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ አዳንኋችሁ ፥ ከፊ
ታችሁም ፡ አሳደድኋቸው ፥ አገራቸውንም ፡
፲፤ ሰጠኋችሁ ፤ እናንተንም ፡— እኔ ፡ አምላካችሁ ፡
እግዚአብሔር ፡ ነኝ ፤ በምድራቸው ፡ የተቀመ
ጣችሁባቸውን ፡ የአሞራውያንን ፡ አማልክት ፡
አትፍሩ ፡ አልኋችሁ ። እናንተ ፡ ግን ፡ ድም
ፄን ፡ አልሰማችሁም ።

፲፩፤ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ መጥቶ ፡ በዖ
ፍራ ፡ ባለችው ፡ ለአቢዔዝራዊው ፡ ለኢዮአስ ፡
በነበረችው ፡ በአድባሩ ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ ተቀ
መጠ ፤ ልጁም ፡ ጌዴዎን ፡ ከምድያማውያን ፡
ለመሸሸግ ፡ በወይን ፡ መጥመቂያው ፡ ውስጥ ፡
፲፪፤ስንዴ ፡ ይወቃ ፡ ነበር ። የእግዚአብሔርም ፡
መልአክ ፡ ለእርሱ ፡ ተገልጦ ፡— አንተ ፡ ጽኑዕ ፡
ኃያል ፡ ሰው ፥ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡
፲፫፤ ነው ፡ አለው ። ጌዴዎንም ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥
እግዚአብሔር ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ከሆነ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡
ሁሉ ፡ ለምን ፡ ደረሰብን ? አባቶቻችንስ ፡— እግ
ዚአብሔር ፡ ከግብፅ ፡ አውጥቶናል ፡ ብለው ፡
ይነግሩን ፡ የነበረ ፡ ተአምራቱ ፡ ወዴት ፡ አለ ?
አሁን ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ትቶናል ፥ በምድ
ያማውያንም ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶናል ፡ አለው ።
፲፬፤ እግዚአብሔርም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡—
በዚህ ፡ በጕልበትህ ፡ ሂድ ፥ እስራኤልንም ፡ ከም
ድያም ፡ እጅ ፡ አድን ፤ እነሆ ፥ ልኬሃለሁ ፡ አለው ።
፲፭፤ እርሱም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ እስራኤልን ፡ በምን ፡
አድናለሁ ? ወገኔ ፡ ከምናሴ ፡ ነገድ ፡ ከሁሉ ፡
ይልቅ ፡ የተጠቃ ፡ ነው ፤ እኔም ፡ በአባቴ ፡ ቤት ፡
፲፮፤ የሁሉ ፡ ታናሽ ፡ ነኝ ፡ አለው ። እግዚአብሔ
ርም ፡— በእርግጥ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ እሆናለሁ ፥
ምድያምንም ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ አድርገህ ፡
፲፯፤ ትመታለህ ፡ አለው ። እርሱም ፡— በአንተ ፡
ዘንድ ፡ ሞገስ ፡ ካገኘሁ ፥ የምትናገረኝም ፡ አንተ ፡
፲፰፤ እንደ ፡ ሆንህ ፡ ምልክት ፡ አሳየኝ ፤ ወደ ፡ አን
ተም ፡ እስክመለስ ፡ ድረስ ፥ ቍርባኔንም ፡ አም
ጥቼ ፡ እስካቀርብልህ ፡ ድረስ ፥ እባክህ ፥ ከዚህ ፡
አትላወስ ፡ አለው ። እርሱም ፡— እስክትመ
፲፱፤ ለስ ፡ ድረስ ፡ እቆያለሁ ፡ አለ ። ጌዴዎን ፡ ገባ ፡
የፍየሉንም ፡ ጠቦት ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያም ፡
ዱቄት ፡ የቂጣ ፡ እንጎቻ ፡ አዘጋጀ ፤ ሥጋውን ፡
በሌማት ፡ አኖረ ፥ መረቁንም ፡ በምንቸት ፡ ውስጥ ፡
አደረገ ፥ ሁሉንም ፡ ይዞ ፡ በአድባሩ ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡
አቀረበለት ። ፳፤ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡—
ሥጋውንና ፡ የቂጣውን ፡ እንጎቻ ፡ ወስደህ ፡
በዚህ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ አኑር ፥ መረቁንም ፡ አፍ
ስስ ፡ አለው ። እንዲሁም ፡ አደረገ ። ፳፩፤ የእግዚ
አብሔርም ፡ መልአክ ፡ በእጁ ፡ ያለውን ፡ የበት
ሩን ፡ ጫፍ ፡ ዘርግቶ ፡ ሥጋውንና ፡ የቂጣውን ፡
እንጎቻ ፡ አስነካ ፤ እሳትም ፡ ከድንጋዩ ፡ ውስጥ ፡
ወጥቶ ፡ ሥጋውንና ፡ የቂጣውን ፡ እንጎቻ ፡ በላ ።
የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ከዓይኑ ፡ ተሰወረ ።
ጌዴዎንም ፡ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ እንደ ፡ ፳፪፤
ሆነ ፡ አየ ፤ ጌዴዎንም ፡— አቤቱ ፡ አምላኬ ፡
ሆይ ፥ ወዮልኝ ፤ የእግዚአብሔርን ፡ መልአክ ፡
ፊት ፡ ለፊት ፡ አይቻለሁና ፡ አለ ። ፳፫፤ እግዚአብሔ
ርም ፡— ሰላም ፡ ለአንተ ፡ ይሁን ፤ አትፍራ ፤
አትሞትም ፡ አለው ። ፳፬፤ ጌዴዎንም ፡ በዚያ ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ሠራ ፥ ስሙንም ፡—
እግዚአብሔር ፡ ሰላም ፡ ብሎ ፡ ጠራው ። እር
ሱም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ለአቢዔዝራውያን ፡
በምትሆነው ፡ በዖፍራ ፡ አለ ።

፳፭፤ እግዚአብሔርም ፡ በዚያ ፡ ሌሊት ፡— የአባት
ህን ፡ በሬ ፥ ሰባት ፡ ዓመት ፡ የሆነውን ፡ ሁለተ
ኛውን ፡ በሬ ፥ ውሰድ ፥ የአባትህ ፡ የሆነው
ንም ፡ የበአል ፡ መሠዊያ ፡ አፍርስ ፥ በእርሱም ፡
ዙሪያ ፡ ያለውን ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀድ ፡ ቍረጥ ፤
፳፮፤ በዚያም ፡ ኮረብታ ፡ አናት ፡ ላይ ፡ ለአምላክህ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ አሳምረህ ፡ ሥራ ፤
ሁለተኛውንም ፡ በሬ ፡ ውሰድ ፥ በዚያም ፡ በቈ
ረጥኸው ፡ በማምለኪያ ፡ ዐፀዱ ፡ እንጨት ፡ ላይ ፡
የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ አቅርብ ፡ አለው ።
፳፯፤ ጌዴዎንም ፡ ከባሪያዎቹ ፡ አሥር ፡ ሰዎችን ፡ ወስዶ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዳለው ፡ አደረገ ፤ የአባቱን ፡
ቤተ ፡ ሰቦች ፡ የከተማውንም ፡ ሰዎች ፡ ስለ ፡ ፈራ ፡
ይህን ፡ በቀን ፡ ለማድረግ ፡ አልቻለም ፥ ነገር ፡
ግን ፡ በሌሊት ፡ አደረገው ።

፳፰፤ የከተማውም ፡ ሰዎች ፡ ማልደው ፡ ተነሡ ፥
እነሆም ፥ የበአል ፡ መሠዊያ ፡ ፈርሶ ፥ በዙሪ
ያው ፡ ያለውም ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀድ ፡ ተቈ
ርጦ ፥ በተሠራውም ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ ሁለተ
ኛው ፡ በሬ ፡ ተሠውቶ ፡ አገኙት ። ፳፱፤ እርስ ፡ በር
ሳቸውም ፡— ይህን ፡ ነገር ፡ ያደረገ ፡ ማን ፡ ነው ?
ተባባሉ ። በጠየቁና ፡ በመረመሩም ፡ ጊዜ ፡—
ይህን ፡ ነገር ፡ ያደረገ ፡ የኢዮአስ ፡ ልጅ ፡ ጌዴ
ዎን ፡ ነው ፡ አሉ ። ፴፤ የከተማውም ፡ ሰዎች ፡
ኢዮአስን ፡— የበአልን ፡ መሠዊያ ፡ አፍርሶአ
ልና ፥ በዙሪያውም ፡ ያለውን ፡ የማምለኪያ ፡
ዐፀድ ፡ ቈርጦአልና ፡ እንዲሞት ፡ ልጅህን ፡
አውጣ ፡ አሉት ። ፴፩፤ ኢዮአስም ፡ እርሱን ፡ የተ
ቃወሙትን ፡ ሁሉ ፡— ለበአል ፡ ትምዋገቱለታ
ላችሁን ? ወይስ ፡ እርሱን ፡ ታድናላችሁን ?
የሚምዋገትለት ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ነገ ፡ ይሙት ፤

እርሱ ፡ አምላክ ፡ ከሆነ ፡ መሠዊያውን ፡ ከፈረ
ሰው ፡ ጋር ፡ ለራሱ ፡ ይምዋገት ፡ አላቸው ፡፡
፴፪ ስለዚህም ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡— መሠዊያውን ፡ አፍ
ርሶአልና ፡ በኣል ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይምዋገት ፡
ብሎ ፡ ጌዴዎንን ፡— ይሩበኣል ፡ ብሎ ፡ ጠራው ፡፡
፴፫ ምድያማውያንም ፡ አማሌቃውያንም ፡ ሁሉ ፡
የምሥራቅም ፡ ሰዎች ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡ ተሰበ
ሰቡ ፤ ዮርዳኖስንም ፡ ተሻገሩ ፤ በኢይዝራኤ
፴፬ ልም ፡ ሸለቆ ፡ ሰፈሩ ፡፡ የእግዚአብሔርም ፡ መን
ፈስ ፡ በጌዴዎን ፡ ገባበት ፤ እርሱም ፡ ቀንደ ፡
መለከቱን ፡ነፋ ፤ የአቢዔዝርም ፡ ሰዎች ፡ ተጠ
፴፭ ርተው ፡ በኋላው ፡ ተከተሉት ፡፡ ወደ ፡ ምና
ሴም ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ መልክተኞችን ፡ ሰደደ ፡
እነርሱም ፡ ደግሞ ፡ ተጠርተው ፡ በኋላው ፡ ተከ
ተሉት ፤ መልክተኞችንም ፡ ወደ ፡ አሴርና ፡ ወደ ፡
ዛብሎን ፡ ወደ ፡ ንፍታሌምም ፡ ሰደደ ፤ እነር
ሱም ፡ ሊገናኙአቸው ፡ ወጡ ፡፡
፴፮ ጌዴዎንም ፡ እግዚአብሔርን ፡— እንደ ፡ ተና
ገርህ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ በእኔ ፡ እጅ ፡
፴፯ ታድን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፤ እነሆ ፤ በአውድማው ፡
ላይ ፡ የተበዘተ ፡ የበግ ፡ ጠጕር ፡ አኖራለሁ ፤ በጠ
ጕሩ ፡ ብቻ ፡ ላይ ፡ ጠል ፡ ቢሆን ፡ በምድሩም ፡
ሁሉ ፡ ደረቅ ፡ ቢሆን ፤ እንደ ፡ ተናገርህ ፡ የእስ
ራኤልን ፡ ልጆች ፡ በእኔ ፡ እጅ ፡ እንድታድና
፴፰ ቸው ፡ አውቃለሁ ፡ አለ ፡፡ እንዲሁም ፡ ሆነ ፤ በነ
ጋውም ፡ ማልዶ ፡ ተነሣ ፤ ጠጕሩንም ፡ ጨመ
ቀው ፤ ከጠጕሩም ፡ የተጨመቀው ፡ ጠል ፡ ቆሬ ፡
፴፱ ሙሉ ፡ ውኃ ፡ ሆነ ፡፡ ጌዴዎንም ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡— እኔ ፡ ይህን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ስናገር ፡ አት
ቈጣኝ ፤ እኔ ፡ ይህን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ በጠጕሩ ፤
እባክህ ፤ ልፈትን ፤ አሁንም ፡ በጠጕሩ ፡ ብቻ ፡
ላይ ፡ ደረቅ ፡ ይሁን ፤ በምድሩም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡
፵ ጠል ፡ ይሁን ፡ አለው ፡፡ እግዚአብሔርም ፡
በዚያ ፡ ሌሊት ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ፤ በጠጕሩ ፡
ብቻ ፡ ላይ ፡ ደረቅ ፡ ነበረ ፤ በምድሩም ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ ጠል ፡ ነበረ ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፯ ፡፡

፩ ጌዴዎን ፡ የተባለውም ፡ ይሩበኣል ፡ ከእር
ሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ማልደው ፡
ተነሡ ፤ በሐሮድ ፡ ምንጭ ፡ አጠገብም ፡ ሰፈሩ ፤
የምድያምም ፡ ሰፈር ፡ ከእነርሱ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡
በኩል ፡ በሞሬ ፡ ኮረብታ ፡ አጠገብ ፡ በሸለቆው ፡
ውስጥ ፡ ነበረ ፡፡
፪ እግዚአብሔርም ፡ ጌዴዎንን ፡— ከአንተ ፡
ጋር ፡ ያለው ፡ ሕዝብ ፡ በዝቶአል ፤ ስለዚህ ፡
እስራኤል ፡— እጄ ፡ አዳነኝ ፡ ብሎ ፡ እንዳይታበ
ይብኝ ፡ እኔ ፡ ምድያምን ፡ በእጃቸው ፡ አሳልፌ ፡
፫ አልሰጣቸውም ፡፡ አሁንም ፡ እንግዲህ ፡— የፈራ ፡
የደነገጠም ፡ ከገለዓድ ፡ ተራራ ፡ ተነሥቶ ፡ ይመ
ለስ ፡ ብለህ ፡ በሕዝቡ ፡ ጆሮ ፡ አውጅ ፡ አለው ፡፡
ከሕዝቡም ፡ ሀያ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ተመለሱ ፤
አሥርም ፡ ሺህ ፡ ቀሩ ፡፡
፬ እግዚአብሔርም ፡ ጌዴዎንን ፡— ሕዝቡ ፡ ገና ፡
ብዙ ፡ ነው ፤ ወደ ፡ ውኃ ፡ አውርዳቸው ፤ በዚ
ያም ፡ እፈትናቸዋለሁ ፤ እኔም ፡— ይህ ፡ ከአ
ንተ ፡ ጋር ፡ ይሂድ ፡ የምለው ፡ እርሱ ፡ ከአንተ ፡
ጋር ፡ ይሄዳል ፤ እኔም ፡— ይህ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡
አይሂድ ፡ የምለው ፡ እርሱ ፡ አይሄድም ፡ አለው ፡፡
፭ ሕዝቡንም ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ አወረደ ፡፡ እግዚአብ
ሔርም ፡ ጌዴዎንን ፡— ውሻ ፡ እንደሚጠጣ ፡
ውኃ ፡ በምላሱ ፡ የሚጠጣውን ፡ ሁሉ ፤ እርሱን ፡
ለብቻው ፡ አድርገው ፤ እንዲሁም ፡ ሊጠጣ ፡
በጕልበቱ ፡ የሚንበረከከውን ፡ ሁሉ ፡ ለብቻው ፡
፮ አድርገው ፡ አለው ፡፡ በእጃቸውም ፡ ውኃ ፡ ወደ ፡
አፋቸው ፡ አድርገው ፡ የጠጡት ፡ ቍጥር ፡
ሦስት ፡ መቶ ፡ ነበረ ፤ የቀሩት ፡ ሕዝብ ፡ ግን ፡
ውኃ ፡ ሊጠጡ ፡ በጕልበታቸው ፡ ተንበረከኩ ፡፡
፯ እግዚአብሔርም ፡ ጌዴዎንን ፡— በእጃቸው ፡
ውኃ ፡ በጠጡት ፡ በሦስት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ አድ
ናችኋለሁ ፤ ምድያማውያንንም ፡ በእጅህ ፡ አሳ
ልፌ ፡ እሰጥሃለሁ ፤ የቀሩት ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡
ግን ፡ ወደ ፡ ስፍራቸው ፡ ይመለሱ ፡ አለው ፡፡
፰ የሕዝቡንም ፡ ስንቅና ፡ ቀንደ ፡ መለከት ፡ በእ
ጃቸው ፡ ወሰዱ ፤ የቀሩትንም ፡ የእስራኤል ፡
ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ድንኳናቸው ፡ ሰደዳቸው ፤
ሦስቱን ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡
ጠበቃቸው ፤ የምድያምም ፡ ሰፈር ፡ ከእርሱ ፡
በታች ፡ በሸለቆው ፡ ውስጥ ፡ ነበረ ፡፡
፱ በዚያም ፡ ሌሊት ፡ እግዚአብሔር ፡— በእ
ጅህ ፡ አሳልፌ ፡ ሰጥቻቸዋለሁና ፡ ተነሥተህ ፡
፲ ወደ ፡ ሰፈር ፡ ውረድ ፡፡ አንተም ፡ ለመውረድ ፡
ብትፈራ ፡ አንተ ፡ ከሎሌህ ፡ ከፉራ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡
፲፩ ሰፈሩ ፡ ውረድ ፤ የሚናገሩትንም ፡ ትሰማለህ ፤
ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ ትወርድ ፡ ዘንድ ፡
እጅህ ፡ ትበረታለች ፡ አለው ፡፡ እርሱና ፡ ሎሌው ፡
ፉራ ፡ በሰፈሩ ፡ ዳርቻ ፡ ወደ ፡ ነበሩት ፡ ሰልፈ
፲፪ ኞች ፡ ወረዱ ፡፡ ብዛታቸውም ፡ እንደ ፡ አንበጣ ፡
የሆነ ፡ ምድያማውያንና ፡ አማሌቃውያን ፡ የም
ሥራቅም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በሸለቆው ፡ ውስጥ ፡
ሰፍረው ፡ ነበር ፤ የግመሎቻቸውም ፡ ብዛት ፡
ቍጥር ፡ እንደሌለው ፡ በባሕር ፡ ዳር ፡ እንዳለ ፡
፲፫ አሸዋ ፡ ነበረ ፡፡ ጌዴዎንም ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡
አንድ ፡ ሰው ፡ ሕልምን ፡ ለባልንጀራው ፡ ሲያ
ጫውት ፡— እነሆ ፤ ሕልም ፡ አለምሁ ፤ እነሆም ፤
አንዲት ፡ የገብስ ፡ እንጐቻ ፡ ወደ ፡ ምድያም ፡
ሰፈር ፡ ተንከባልላ ፡ ወረደች ፤ ወደ ፡ ድንኳኑም ፡
ደርሳ ፡ እስኪወድቅ ፡ ድረስ ፡ መታችው ፤ ገለበ
ጠችውም ፤ ድንኳኑም ፡ ተጋደመ ፡ ይል ፡ ነበር ፡፡
፲፬ ባልንጀራውም ፡ መልሶ ፡— ይህ ፡ ነገር ፡ ከእስ
ራኤል ፡ ሰው ፡ ከኢዮአስ ፡ ልጅ ፡ ከጌዴዎን ፡
ሰይፍ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ አይደለም ፤ እግዚአብ
ሔር ፡ ምድያምንና ፡ ሠራዊቱን ፡ ሁሉ ፡ በእጁ ፡
አሳልፎ ፡ ሰጥቶአል ፡ አለው ፡፡
፲፭ ጌዴዎንም ፡ ሕልሙንና ፡ ትርጓሜውን ፡ በሰማ ፡
ጊዜ ፡ ሰገደ ፤ ወደ ፡ እስራኤልም ፡ ሰፈር ፡ ተመ
ልሶ ፡— እግዚአብሔር ፡ የምድያምን ፡ ሠራዊት ፡
በእጃችሁ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶአልና ፡ ተነሡ ፡ አለ ፡፡

፲፮ ሦስቱንም ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ በሦስት ፡ ወገን ፡ ከፈላቸው ፥ በሁሉም ፡ እጅ ፡ ቀንደ ፡ መለከትና ፡ ባዶ ፡ ማሰሮ ፥ በማሰሮውም ፡ ውስጥ ፡ ችቦ ፡ ሰጠ ። ፲፯ እርሱም ፦ እኔን ፡ ተመልከቱ ፥ እንዲሁም ፡ አድርጉ ፤ እነሆም ፥ ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ ዳርቻ ፡ በደረስሁ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ እንደማደርግ ፡ እንዲሁ ፡ እናንተ ፡ አድርጉ ፤ ፲፰ እኔ ፡ ከእኔም ፡ ጋር ፡ ያሉት ፡ ሁሉ ፡ ቀንደ ፡ መለከት ፡ ስንነፋ ፥ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ በሰፈሩ ፡ ዙሪያ ፡ ሁሉ ፡ ቀንደ ፡ መለከታችሁን ፡ ንፉ ፦ ለእግዚአብሔርና ፡ ለጌዴዎን ፡ በሉ ፡ አላቸው ።

፲፱ ጌዴዎንም ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ በመካከለኛው ፡ ትጋት ፡ ትጋቱም ፡ በተጀመረ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ ዳርቻ ፡ መጡ ፤ ቀንደ ፡ መለከቶችንም ፡ ነፉ ፥ በእጃቸውም ፡ ፳ የነበሩትን ፡ ማሰሮች ፡ ሰበበሩ ። ሦስቱም ፡ ወገኖች ፡ ቀንደ ፡ መለከቶችን ፡ ነፉ ፥ ማሰሮችንም ፡ ሰበሩ ፥ በግራ ፡ እጃቸውም ፡ ችቦችን ፥ በቀኝ ፡ እጃቸውም ፡ ቀንደ ፡ መለከቶችን ፡ ይዘው ፡ እየነፉ ፦ የእግዚአብሔርና ፡ የጌዴዎን ፡ ሰይፍ ፡ ብለው ፡ ጮኹ ። ፳፩ ሁሉም ፡ በየበታው ፡ በሰፈሩ ፡ ዙሪያ ፡ ቆመ ፤ ሠራዊቱም ፡ ሁሉ ፡ ሮጠ ፥ ጮኸ ፥ ሸሸም ። ፳፪ ሦስቱንም ፡ መቶ ፡ ቀንደ ፡ መለከቶች ፡ ነፉ ፥ እግዚአብሔርም ፡ የሰውን ፡ ሁሉ ፡ ሰይፍ ፡ በባልንጀራውና ፡ በሠራዊቱ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አደረገ ፤ ሠራዊቱም ፡ በጽሬራ ፡ በኩል ፡ እስከ ፡ ቤትሺጣ ፡ ድረስ ፡ በጠበት ፡ አጠገብ ፡ እስከለው ፡ እስከ ፡ አቤልምሖላ ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ሸሸ ። ፳፫ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ከንፍታሌምና ፡ ከአሴር ፡ ከምናሴም ፡ ሁሉ ፡ ተሰብስበው ፡ ምድያምን ፡ አሳደዱ ።

፳፬ ጌዴዎንም ፦ ምድያምን ፡ ለመገናኘት ፡ ውረዱ ፥ እስከ ፡ ቤትባራም ፡ ድረስ ፡ ያለውን ፡ ውኃ ፥ ዮርዳኖስን ፥ ያዙባቸው ፡ ብሎ ፡ መልክተኞችን ፡ በኤፍሬም ፡ ወዳለው ፡ ተራራማ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ሰደደ ። የኤፍሬም ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ተሰብስበው ፡ እስከ ፡ ቤትባራ ፡ ድረስ ፡ ውኃውን ፥ ዮርዳኖስን ፥ ያዙ ። ፳፭ የምድያምን ፡ ሁለቱን ፡ መኳንንት ፡ ሔሬብንና ፡ ዜብን ፡ ያዙ ፤ ሔሬብንም ፡ በሔሬብ ፡ ዓለት ፡ አጠገብ ፡ ገደሉት ፥ ዜብንም ፡ በዜብ ፡ መጥመቂያ ፡ ላይ ፡ ገደሉት ፤ ምድያምንም ፡ አሳደዱ ፥ የሔሬብንና ፡ የዜብንም ፡ ራስ ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ወደ ፡ ጌዴዎን ፡ መጡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ የኤፍሬም ፡ ሰዎች ፦ ይህ ፡ ያደረግህብን ፡ ምንድር ፡ ነው ? ምድያምን ፡ ለመዋጋት ፡ በወጣህ ፡ ጊዜ ፡ ለምን ፡ አልጠራኸንም ? አሉት ። ፪ ጽኑ ፡ ጥልም ፡ ተጣሉት ። እርሱም ፦ እኔ ፡ ከደረግሁት ፡ እናንተ ፡ ያደረጋችሁት ፡ አይበልጥምን ? የኤፍሬም ፡ ወይን ፡ ቃርሚያ ፡ ከአቢዔዝር ፡ ወይን ፡ መከር ፡ አይሻልምን ? ፫ እግዚአብሔር ፡ የምድያምን ፡ መኳንንት ፡ ሔሬብንና ፡ ዜብን ፡ በእጃችሁ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶአቸዋል ፤ እናንተ ፡ ያደረጋችሁትን ፡ የሚመስል ፡ እኔ ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡ እችል ፡ ኖሮአል ? አላቸው ። ይህን ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ፡ ቍጣቸው ፡ በረደ ።

፬ ጌዴዎንም ፡ ከሦስቱ ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ደርሶ ፡ ተሻገረ ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ ቢደክሙ ፡ ያሳድዱ ፡ ነበር ። ፭ የሱኮትንም ፡ ሰዎች ፦ የምድያምን ፡ ነገሥታት ፡ ዛብሄልንና ፡ ስልማናን ፡ ሳሳድድ ፥ ደክመዋልና ፡ እኔን ፡ ለተከተሉ ፡ ሕዝብ ፡ እንጀራ ፥ እባካችሁ ፥ ስጡ ፡ አላቸው ። ፮ የሱኮትም ፡ አለቆች ፦ እኛ ፡ ለሠራዊትህ ፡ እንጀራ ፡ እንድንሰጥ ፡ የዛብሄልና ፡ የስልማና ፡ እጅ ፡ አሁን ፡ በእጅህ ፡ ነውን ? አሉ ። ፯ ጌዴዎንም ፦ እግዚአብሔር ፡ ዛብሄልንና ፡ ስልማናን ፡ በእጄ ፡ አሳልፎ ፡ ሲሰጠኝ ፡ እኔ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ እሾህና ፡ በኵርንችት ፡ ሥጋችሁን ፡ እገርፋለሁ ፡ አለ ። ፰ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ጵኒኤል ፡ ወጣ ፥ ለጵኒኤልም ፡ ሰዎች ፡ እንዲሁ ፡ አላቸው ፤ የጵኒኤልም ፡ ሰዎች ፡ የሱኮት ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ መለሱ ፡ መለሱለት ። ፱ እርሱም ፡ የጵኒኤልን ፡ ሰዎች ፡ ደግሞ ፦ በደኅና ፡ በተመለስሁ ፡ ጊዜ ፡ ይህን ፡ ግንብ ፡ አፈርሰዋለሁ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ።

፲ ዛብሄልና ፡ ስልማናም ፡ ከሠራዊቶቻቸው ፡ ጋር ፡ በቀርቀር ፡ ነበሩ ፤ ሰይፍ ፡ የሚመዝዙ ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ወድቀው ፡ ነበርና ፡ ከምሥራቅ ፡ ሰዎች ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ የቀሩ ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ያህል ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ። ፲፩ ጌዴዎንም ፡ የድንኳን ፡ ተቀማጮች ፡ በሉበት ፡ መንገድ ፡ በኖባህና ፡ በዮግብሃ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ወጣ ፤ ሠራዊቱም ፡ ተዘልሎ ፡ ነበርና ፡ ሠራዊቱን ፡ መታ ። ፲፪ ዛብሄልና ፡ ስልማናም ፡ ሸሹ ፤ እርሱም ፡ አሳደዳቸው ፥ ሁለቱንም ፡ የምድያም ፡ ነገሥታት ፡ ዛብሄልንና ፡ ስልማናን ፡ ያዘ ፥ ሠራዊቱንም ፡ ሁሉ ፡ አስደነገጠ ።

፲፫ የኢዮአስ ፡ ልጅም ፡ ጌዴዎን ፡ ከሔሬስ ፡ ዳገት ፡ ከሰልፍ ፡ ተመለሰ ። ፲፬ ከሱኮትም ፡ ሰዎች ፡ አንድ ፡ ብላቴና ፡ ይዞ ፡ ጠየቀው ፤ እርሱም ፡ የሱኮትን ፡ አለቆችና ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሰባ ፡ ሰባት ፡ ሰዎች ፡ ጻፈለት ። ፲፭ ወደ ፡ ሱኮትም ፡ ሰዎች ፡ መጥቶ ፦ ለደከሙት ፡ ሰዎችህ ፡ እንጀራ ፡ እንሰጥ ፡ ዘንድ ፡ የዛብሄልና ፡ የስልማና ፡ እጅ ፡ አሁን ፡ በእጅህ ፡ ነውን ? ብላችሁ ፡ የተላገዳችሁብኝ ፥ ዛብሄልና ፡ ስልማና ፡ እነሆ ፥ አለ ። ፲፮ የከተማይቱንም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ያዘ ፥ የምድረ ፡ በዳንም ፡ እሾህና ፡ ኵርንችት ፡ ወስዶ ፡ የሱኮትን ፡ ሰዎች ፡ ገረፋቸው ። ፲፯ የጵኒኤልንም ፡ ግንብ ፡ አፈረሰ ፥ የከተማይቱንም ፡ ሰዎች ፡ ገደላቸው ።

፲፰ ዛብሄልንና ፡ ስልማናን ፦ በታቦር ፡ የገደላችኋቸው ፡ ሰዎች ፡ እንዴት ፡ ያሉ ፡ ነበሩ ? አላቸው ። እነርሱም ፦ እንደ ፡ አንተ ፡ ያሉ ፡ ነበሩ ፥ አንተንም ፡ ይመስሉ ፡ ነበር ፤ መልካቸውም ፡ እንደ ፡ ንጉሥ ፡ ልጆች ፡ መልክ ፡ ነበረ ፡ ብለው ፡ መለሱለት ። ፲፱ እርሱም ፦ የእናቴ ፡ ልጆች ፡

ወንድሞቼ ፡ ነበሩ ፤ አድናችኋቸው ፡ ቢሆን ፡
ኖሮ ÷ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! እኔ ፡ አልገድላ
፳ ፡ ችሁም ፡ ነበር ፡ አለ ። በኵሩንም ፡ ዬቴርን ፡—
ተነሥተህ ፡ ግደላቸው ፡ አለው ፤ ብላቴናው ፡
ግን ፡ ገና ፡ ብላቴና ፡ ነበረና ፡ ስለ ፡ ፈራ ፡ ሰይ
፳፩ ፡ ፉን ፡ አልመዘዘም ። ዛብሄልና ፡ ስልማናም ፡—
የሰው ፡ ኃይሉ ፡ እንደ ፡ ሰውነቱ ፡ ነውና ፡ አንተ ፡
ተነሥተህ ፡ ውደቅብን ፡ አሉት ። ጌዴዎንም ፡
ተነሥቶ ፡ ዛብሄልንና ፡ ስልማናን ፡ ገደለ ÷ በግ
መሎቻቸውም ፡ አንገት ፡ የነበሩትን ፡ ሥሉሴ
ዎች ፡ ማረከ ።
፳፪ ፡ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ጌዴዎንን ፡— ከምድ
ያም ፡ እጅ ፡ አድነኸናልና ፡ አንተ ፡ ልጅህም ፡
፳፫ ፡ የልጅ ፡ ልጅህም ፡ ደግሞ ፡ ግዛን ፡ አሉት ። ጌዴ
ዎንም ፡— እኔ ፡ አልገዛችሁም ÷ ልጄም ፡ አይገ
ዛችሁም ፤ እግዚአብሔር ፡ ይገዛችኋል ፡ አላ
፳፬ ፡ ቸው ። እስማኤላውያንም ፡ ስለ ፡ ነበሩ ፡ የወ
ርቅ ፡ ጕትቻ ፡ ነበራቸውና ፡ ጌዴዎን ፡— ሁላ
ችሁ ፡ ከምርኮአችሁ ፡ ጕትቻችሁን ፡ እንድትሰ
፳፭ ፡ ጡኝ ፡ እለምናችኋለሁ ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡—
ፈቅደን ፡ እንሰጥሃለን ፡ ብለው ፡ መለሱለት ።
መጐናጸፊያም ፡ አነጠፉ ÷ ሰውም ፡ ሁሉ ፡ የም
፳፮ ፡ ርኮውን ፡ ጕትቻ ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ ጣለ ። የለመነ
ውም ፡ የወርቅ ፡ ጕትቻ ፡ ሚዛኑ ÷ ከአምባሩ ÷
ከድሪውም ÷ የምድያምም ፡ ነገሥታት ፡ ከለበ
ሱት ፡ ከቀዩ ፡ ቀሚስ ÷ በግመሎቻቸውም ፡ አን
ገት ፡ ከነበሩት ፡ ሥሉሴዎች ፡ ሌላ ÷ ሺህ ፡ ሰባት ፡
፳፯ ፡ መቶ ፡ ሰቅለ ፡ ወርቅ ፡ ነበረ ። ጌዴዎንም ፡ ኤፉድ ፡
አድርጎ ፡ አሠራው ÷ በከተማውም ፡ በዖፍራ ፡
አኖረው ፤ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ተከትሎ ፡ አመ
ነዘረበት ፤ ለጌዴዎንና ፡ ለቤቱም ፡ ወጥመድ ፡
፳፰ ፡ ሆነ ። ምድያምም ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተዋ
ረደ ÷ ራሳቸውንም ፡ ዳግመኛ ፡ አላነሡም ፤ በጌ
ዴዎንም ፡ ዕድሜ ፡ ምድሪቱ ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡
ዐረፈች ።
፳፱ ፡ የኢዮአስም ፡ ልጅ ፡ ይሩበአል ፡ ሄዶ ፡ በቤቱ ፡
፴ ፡ ተቀመጠ ። ለጌዴዎንም ፡ ብዙ ፡ ሚስቶች ፡ ነበ
ሩትና ፡ ከወገቡ ፡ የወጡ ፡ ሰባ ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ።
፴፩ ፡ በሴኬምም ፡ የነበረችው ፡ ቁባቱ ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡
ወለደችለት ÷ ስሙንም ፡ አቤሜሌክ ፡ ብሎ ፡
፴፪ ፡ ጠራው ። የኢዮአስም ፡ ልጅ ፡ ጌዴዎን ፡ በመ
ልካም ፡ ሽምግልና ፡ ሞተ ÷ በአቢዔዝራውያ
ንም ፡ ከተማ ፡ በዖፍራ ፡ በነበረችው ፡ በአባቱ ፡
በኢዮአስ ፡ መቃብር ፡ ተቀበረ ።
፴፫ ፡ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ጌዴዎን ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተመለሱ ÷ በኣሊምንም ፡
ተከትለው ፡ አመነዘሩ ፤ በኣልብሪትንም ፡ አም
፴፬ ፡ ላካቸው ፡ አደረጉ ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
በዙሪያቸው ፡ ከነበሩት ፡ ከጠላቶቻቸው ፡ ሁሉ ፡
እጅ ፡ ያዳናቸውን ፡ አምላካቸውን ፡ እግዚአብ
፴፭ ፡ ሔርን ፡ አላሰቡትም ፤ እርሱም ፡ ለእስራኤል ፡
በጎ ፡ ነገርን ፡ ሁሉ ፡ እንዳደረገ ፡ መጠን ÷ እነርሱ ፡
ለጌዴዎን ፡ ለይሩበአል ፡ ቤት ፡ ወረታ ፡ አላደረ
ጉም ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

የይሩበአል ፡ ልጅ ፡ አቤሜሌክም ፡ ወደ ፡ ፩ ፡
ሴኬም ፡ ወደ ፡ እናቱ ፡ ወንድሞች ፡ ሄደ ÷ ለእ
ነርሱም ፡ ለእናቱ ፡ አባት ፡ ቤተ ፡ ሰቦችም ፡
ሁሉ ፡— በሴኬም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ጆሮ ፡— ፪ ፡
ሰባ ፡ የሆኑት ፡ የይሩበአል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ቢገ
ዙአችሁ ፡ ወይስ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ቢገዛችሁ ፡
ምን ፡ ይሻላችኋል ? ብላችሁ ፡ ንገሩአቸው ፡
ብዬ ፡ እለምናችኋለሁ ፤ ደግሞ ፡ እኔ ፡ የአጥን
ታችሁ ፡ ፍላጭ ፡ የሥጋችሁ ፡ ቍራጭ ፡ እንደ ፡
ሆንሁ ፡ አስቡ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ። የእና ፫ ፡
ቱም ፡ ወንድሞች ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡
እርሱ ፡ በሴኬም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ጆሮ ፡ ተናገሩ ፤
እነርሱም ፡— እርሱ ፡ ወንድማችን ፡ ነው ፡ ብለው ፡
አቤሜሌክን ፡ ለመከተል ፡ ልባቸውን ፡ አዘነበ
ሉት ። ከበአልብሪትም ፡ ቤት ፡ ሰባ ፡ ብር ፡ ፬ ፡
ሰጡት ፤ በዚያም ፡ አቤሜሌክ ፡ ምናምንቴዎች
ንና ፡ ወሮበሎችን ፡ ቀጠረበት ÷ እነርሱም ፡ ተከ
ተሉት ። ወደ ፡ አባቱም ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ዖፍራ ፡ ፭ ፡
ሄደ ፤ ሰባ ፡ የሆኑትን ፡ የይሩበአልን ፡ ልጆች ፡
ወንድሞቹን ፡ በአንድ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ አረዳ
ቸው ፤ ትንሹ ፡ የይሩበአል ፡ ልጅ ፡ ኢዮአታም ፡
ግን ፡ ተሸሽጎ ፡ ነበርና ፡ ተረፈ ። የሴኬምም ፡ ፮ ፡
ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ቤትሚሎም ፡ ሁሉ ፡ ተሰበሰቡ ÷
ሄደውም ፡ በሴኬም ፡ በዓምዱ ፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡
በአድባሩ ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ አቤሜሌክን ፡ አነገሡ ።
ይህንም ፡ ነገር ፡ ለኢዮአታም ፡ በነገሩት ፡ ፯ ፡
ጊዜ ÷ ሄዶ ፡ በገሪዛን ፡ ተራራ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ቆመ ÷
ድምፁንም ፡ አንሥቶ ፡ ጮኸ ÷ እንዲህም ፡ አላ
ቸው ፡— የሴኬም ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ÷ እግዚአብሔር ፡
እንዲሰማችሁ ፡ ስሙኝ ። አንድ ፡ ጊዜ ፡ ዛፎች ፡ ፰ ፡
በላያቸው ፡ ንጉሥ ፡ ሊያነግሡ ፡ ሄዱ ፤ ወይራ
ውንም ፡— በእኛ ፡ ላይ ፡ ንገሥ ፡ አሉት ። ወይ ፱ ፡
ራው ፡ ግን ፡— እግዚአብሔርና ፡ ሰዎች ፡ በእኔ ፡
የሚከበሩበትን ፡ ቅባቴን ፡ ትቼ ፡ በዛፎች ፡ ላይ ፡
እንድሰፍፍ ፡ ልሂድ ? አላቸው ። ዛፎችም ፡ በለ ፲ ፡
ሱን ፡— መጥተህ ፡ በላያችን ፡ ንገሥ ፡ አሉት ።
በለሱ ፡ ግን ፡— ጣፋጭነቴንና ፡ መልካሙን ፡ ፲፩ ፡
ፍሬዬን ፡ ትቼ ፡ በዛፎች ፡ ላይ ፡ እንድሰፍፍ ፡
ልሂድ ? አላቸው ። ዛፎችም ፡ ወይኑን ፡— መጥ ፲፪ ፡
ተህ ፡ በላያችን ፡ ንገሥ ፡ አሉት ። ወይኑም ፡— ፲፫ ፡
እግዚአብሔርንና ፡ ሰውን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡
የወይን ፡ ጠጄን ፡ ትቼ ፡ በዛፎች ፡ ላይ ፡ እንድ
ሰፍፍ ፡ ልሂድ ? አላቸው ። ዛፎችም ፡ ሁሉ ፡ እሾ ፲፬ ፡
ህን ፡— መጥተህ ፡ በላያችን ፡ ንገሥ ፡ አሉት ።
እሾሁም ፡ ዛፎችን ፡— በእውነት ፡ እኔን ፡ በእና ፲፭ ፡
ንተ ፡ ላይ ፡ ታነግሡኝ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ኑ ፡ ከጥላዬ ፡
በታች ፡ ተጠጉ ። እንዲሁም ፡ ባይሆን ፡ እሳት ፡
ከእሾህ ፡ ይውጣ ÷ የሊባኖስንም ፡ ዝግባ ፡ ያቃ
ጥል ፡ አላቸው ። አሁን ፡ እንግዲህ ፡ አቤሜሌ ፲፮ ፡
ክን ፡ በማንገሣችሁ ፡ እውነትንና ፡ ቅንነትን ፡
አድርጋችሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ ለይሩበአልም ፡ ለቤ
ቱም ፡ በጎ ፡ አድርጋችሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ እንዳደ

ረገውም ፡ መጠን ፡ ለእርሱ ፡ የተገባውን ፡ አድ
፲፯ ርጋችሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ አባቴ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡
ተጋድሎ ፡ ነበርና ፥ ከምድያምም ፡ እጅ ፡ ሊያ
ድናችሁ ፡ ነፍሱን ፡ ለሞት ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶ ፡
፲፰ ነበርና ፥ እናንተም ፡ ዛሬ ፡ በአባቴ ፡ ቤት ፡ ተነሥ
ታችኋልና ፥ ሰባ ፡ የሆኑትን ፡ ልጆቹንም ፡ በአ
ንድ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ አርዳችኋልና ፥ ወንድማ
ችሁም ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የባሪያይቱን ፡ ልጅ ፡ አቤሜ
ሌክን ፡ በሴኬም ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ አንግሣችኋ
፲፱ ልና ፥ እንግዲህ ፡ ለይሩባአልና ፡ ለቤቱ ፡ እው
ነትንና ፡ ቅንነትን ፡ ዛሬ ፡ አድርጋችሁ ፡ እንደ ፡
ሆነ ፥ በአቤሜሌክ ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፥ እርሱ ፡
፳ ደግሞ ፡ በእናንተ ፡ ደስ ፡ ይበለው ፤ እንዲህ ፡
ባይሆን ፡ ግን ፡ ከአቤሜሌክ ፡ እሳት ፡ ይውጣ ፥
የሴኬምንም ፡ ሰዎች ፡ ቤትሚሎንም ፡ ይብላ ፤
ከሴኬምም ፡ ሰዎች ፡ ከቤትሚሎም ፡ እሳት ፡
፳፩ ይውጣ ፥ አቤሜሌክንም ፡ ይብላ ። ኢዮአታ
ምም ፡ ሸሽቶ ፡ አመለጠ ፥ ወንድሙንም ፡ አቤ
ሜሌክን ፡ ፈርቶ ፡ ወደ ፡ ብኤር ፡ ሄደ ፥ በዚ
ያም ፡ ተቀመጠ ።

፳፪ አቤሜሌክም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ሦስት ፡
፳፫ ዓመት ፡ ነገሠ ። እግዚአብሔር ፡ በአቤሜሌክና
በሴኬም ፡ ሰዎች ፡ መካከል ፡ ክፉን ፡ መንፈስ ፡
ሰደደ ፤ የሴኬምም ፡ ሰዎች ፡ በአቤሜሌክ ፡
፳፬ ላይ ፡ ተንኰል ፡ አደረጉ ። ይህም ፡ የሆነው ፥
በሰባ ፡ የይሩባአል ፡ ልጆቹ ፡ ላይ ፡ የተደረ
ገው ፡ ዓመፅ ፡ እንዲመጣ ፥ ደማቸውም ፡ በገደ
ላቸው ፡ በወንድማቸው ፡ በአቤሜሌክ ፡ ላይ ፥
ወንድሞቹንም ፡ እንዲገድል ፡ እጆቹን ፡ ባጸኑ
አቸው ፡ በሴኬም ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ እንዲሆን ፡
፳፭ ነው ። የሴኬምም ፡ ሰዎች ፡ በተራሮች ፡ ራስ ፡
ላይ ፡ ድብቅ ፡ ጦር ፡ አደረጉ ፥ መንገድ ፡ ተላ
ላፊዎችንም ፡ ሁሉ ፡ ይዘርፉ ፡ ነበር ፤ አቤሜሌ
ክም ፡ ይህን ፡ ወሬ ፡ ሰማ ።

፳፮ የአቤድም ፡ ልጅ ፡ ገዓል ፡ ከወንድሞቹ ፡ ጋር ፡
መጥቶ ፡ ወደ ፡ ሴኬም ፡ ገባ ፤ የሴኬምም ፡ ሰዎች ፡
፳፯ ታመኑበት ። ወደ ፡ እርሻውም ወጡ ፡ ወይና
ቸውንም ፡ ለቀሙ ፥ ጠመቁትም ፥ የደስታም ፡
በዓል ፡ አደረጉ ፤ ወደ ፡ አምላካቸውም ፡ ቤት ፡
ገቡ ፥ በሉም ፡ ጠጡም ፥ አቤሜሌክንም ፡
፳፰ ሰደቡ ። የአቤድም ፡ ልጅ ፡ ገዓል ፡— የምንገ
ዛለት ፡ አቤሜሌክ ፡ ማን ፡ ነው ? ሴኬምስ ፡ ምን
ድር ፡ ነው ? እርሱ ፡ የይሩባአል ፡ ልጅ ፡ አይደለ
ምን ? ዜቡልም ፡ የእርሱ ፡ ሹም ፡ አይደለምን ?
ለሴኬም ፡ አባት ፡ ለኤሞር ፡ ሰዎች ፡ ተገዙ ፤
፳፱ ስለ ፡ ምንስ ፡ ለዚህ ፡ እንገዛለን ? ይህ ፡ ሕዝብ ፡
ከእጄ ፡ በታች ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ አቤሜሌክን ፡
አሳድደው ፡ ነበር ፡ አለ ። አቤሜሌክንም ፡—
ሠራዊትህን ፡ አብዝተህ ፡ ና ፥ ውጣ ፡ አለው ።

፴ የከተማይቱ ፡ ገዥ ፡ ዜቡልም ፡ የአቤድን ፡
ልጅ ፡ የገዓልን ፡ ቃል ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡
፴፩ ተቈጣ ። እንዲህም ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ አቤሜሌክ ፡
በተንኰል ፡ መልክተኞች ፡ ላከ ፡— እነሆ ፥ የአ
ቤድ ፡ ልጅ ፡ ገዓልና ፡ ወንድሞቹ ፡ ወደ ፡ ሴኬም ፡
መጥተዋል ፥ በአንተም ፡ ላይ ፡ ከተማይቱን ፡ አሸ
፴፪ ፍተዋል ። አሁንም ፡ አንተና ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡
ያሉት ፡ ሕዝብ ፡ በሌሊት ፡ ተነሡ ፥ በሜዳም ፡
፴፫ ሸምቁ ፤ ነገም ፡ ፀሐይ ፡ በወጣች ፡ ጊዜ ፡ ማል
ደህ ፡ ተነሣ ፥ በከተማይቱም ፡ ላይ ፡ ውደቅ
ባት ፤ እነሆም ፥ እርሱና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ያሉት ፡
ሕዝብ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፡ እጅህ ፡
እንዳገኘች ፡ አድርግባት ።

፴፬ አቤሜሌክና ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ያሉ ፡ ሕዝብ ፡
ሁሉ ፡ በሌሊት ፡ ተነሡ ፥ በሴኬምም ፡ አቅራ
፴፭ ቢያ ፡ በአራት ፡ ወገን ፡ ሸመቁበት ። የአቤድም ፡
ልጅ ፡ ገዓል ፡ ወጥቶ ፡ በከተማይቱ ፡ በር ፡ አደባ
ባይ ፡ ቆመ ፤ አቤሜሌክና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ያሉት ፡
፴፮ ሕዝብ ፡ ከሸመቁበት ፡ ስፍራ ፡ ተነሡ ። ገዓልም ፡
ሕዝቡን ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ዜቡልን ፡— እነሆ ፥ ከተ
ራሮች ፡ ራስ ፡ ሕዝብ ፡ ይወርዳል ፡ አለው ።
ዜቡልም ፡— ሰዎች ፡ የሚመስለውን ፡ የተራሮ
፴፯ ችን ፡ ጥላ ፡ ታያለህ ፡ አለው ። ገዓልም ፡ ደግሞ ፡—
እነሆ ፥ ሕዝብ ፡ በምድር ፡ መካከል ፡ ይወርዳል ፤
አንድም ፡ ወገን ፡ በምዖንኒም ፡ በአድባሩ ፡
ዛፍ ፡ መንገድ ፡ ይመጣል ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ።
፴፰ ዜቡልም ፡— እንገዛለት ፡ ዘንድ ፡ አቤሜሌክ ፡
ማን ፡ ነው ? ያልህበት ፡ አፍህ ፡ አሁን ፡ የት ፡
አለ ? ይህ ፡ የናቅኸው ፡ ሕዝብ ፡ አይደለምን ?
አሁንም ፡ ወጥተህ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ተዋጋ ፡
፴፱ አለው ። ገዓልም ፡ በሴኬም ፡ ሰዎች ፡ ፊት ፡
፵ ወጣ ፥ ከአቤሜሌክም ፡ ጋር ፡ ተዋጋ ። አቤሜ
ሌክም ፡ አሳደደው ፤ በፊቱም ፡ ሸሸ ፥ እስከ ፡
በሩም ፡ አደባባይ ፡ ድረስ ፡ ብዙዎች ፡ ተጐድ
ተው ፡ ወደቁ ።

፵፩ አቤሜሌክም ፡ በአሩማ ፡ ተቀመጠ ፤ ዜቡ
ልም ፡ ገዓልንና ፡ ወንድሞቹን ፡ በሴኬም ፡ እንዳ
፵፪ ይኖሩ ፡ አሳደዳቸው ። በነጋውም ፡ ሕዝቡ ፡
ወደ ፡ እርሻ ፡ ወጡ ፤ አቤሜሌክም ፡ ሰማ ።
፵፫ ሕዝቡንም ፡ ወስዶ ፡ በሦስት ፡ ወገን ፡ ከፈላ
ቸው ፥ በሜዳም ፡ ሸመቀ ፤ ተመለከተም ፥
እነሆም ፥ ሕዝቡ ፡ ከከተማ ፡ ወጡ ፥ ተነሣባቸ
፵፬ ውም ፡ መታቸውም ። አቤሜሌክም ፡ ከእር
ሱም ፡ ጋር ፡ ያሉት ፡ ወገኖች ፡ ተጣደፉ ፡ በከተ
ማይቱም ፡ በር ፡ አደባባይ ፡ ቆሙ ፤ ሁለቱም ፡
ወገኖች ፡ በእርሻው ፡ ውስጥ ፡ በነበሩት ፡ ሁሉ ፡
፵፭ ላይ ፡ ሮጡባቸው ፥ መቱአቸውም ። አቤሜሌ
ክም ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ሁሉ ፡ ከከተማይቱ ፡ ጋር ፡
ተዋጋ ፤ ከተማይቱንም ፡ ያዘ ፡ በእርስዋ ፡ የነበሩ
ትን ፡ ሕዝብ ፡ ገደለ ፤ ከተማይቱንም ፡ አፈረሰ ፥
ጨውም ፡ ዘራባት ።

፵፮ በሴኬምም ፡ ግንብ ፡ ውስጥ ፡ የነበሩ ፡ ሰዎች ፡
ሁሉ ፡ ይህን ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ኤልብሪት ፡
፵፯ ቤት ፡ ወደ ፡ ምሽጉ ፡ ውስጥ ፡ ገቡ ። አቤሜሌ
ክም ፡ በሴኬም ፡ ግንብ ፡ ውስጥ ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡
ሁሉ ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡ እንደ ፡ ተሰበሰቡ ፡ ሰማ ።
፵፰ አቤሜሌክና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ያሉትም ፡ ሕዝብ ፡
ሁሉ ፡ ወደ ፡ ሰልሞን ፡ ተራራ ፡ ወጡ ፤ አቤሜ
ሌክም ፡ በእጁ ፡ መጥረቢያ ፡ ወስዶ ፡ የዛፉን ፡ ቅር

ንጫፍ ፡ ቈረጠ ፥ አንሥቶም ፡ በጫንቃው ፡ ላይ ፡ አደረገው ፤ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ለነበሩት ፡ ሕዝብ ፡ — እኔ ፡ ሳደርግ ፡ ያያችሁትን ፥ እናንተም ፡ ፈጥናችሁ ፡ እኔ ፡ እንዳደረግሁ ፡ አድርጉ ፡ አላቸው ። ፵፱ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ እያንዳንዳቸው ፡ የዛፉን ፡ ቅርንጫፎች ፡ ቈረጡ ፥ አቤሜሌክንም ፡ ተከትለው ፡ በምሽጉ ፡ ዙሪያ ፡ አኖሩአቸው ፥ ምሽጉንም ፡ በላያቸው ፡ አቃጠሉት ፤ የሴኬምም ፡ ግንብ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ደግሞ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ የሚያህሉ ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ ሞቱ ።

፶ አቤሜሌክም ፡ ወደ ፡ ቴቤስ ፡ መጣ ፥ ቴቤስንም ፡ ከብቦ ፡ ያዛት ። ፶፩ በከተማይቱም ፡ ውስጥ ፡ ብርቱ ፡ ግንብ ፡ ነበረ ፥ የከተማይቱም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፥ ወንዱና ፡ ሴቱ ፡ ሁሉ ፥ ወደዚያ ፡ ሸሹ ፤ ደጁንም ፡ በኋላቸው ፡ ዘጉ ፥ ወደ ፡ ግንቡም ፡ ሰገነት ፡ ላይ ፡ ወጡ ። ፶፪ አቤሜሌክም ፡ ወደ ፡ ግንቡ ፡ ቀርቦ ፡ ይዋጋ ፡ ነበር ፥ በእሳትም ፡ ሊያቃጥለው ፡ ወደ ፡ ግንቡ ፡ ደጅ ፡ ደረሰ ። ፶፫ አንዲትም ፡ ሴት ፡ በአቤሜሌክ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ የወፍጮ ፡ መጅ ፡ ጣለችበት ፥ አናቱንም ፡ ሰበረችው ። ፶፬ እርሱም ፡ ፈጥኖ ፡ ጋሻ ፡ ዣግሬውን ፡ ጠርቶ ፡ — እኔን ፡ — ሴት ፡ ገደለችው ፡ እንዳይሉ ፡ ሰይፍህን ፡ መዝዘህ ፡ ግደለኝ ፡ አለው ፤ ጕልማሳውም ፡ ወጋው ፥ ሞተም ። ፶፭ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ አቤሜሌክ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ተመለሰ ። ፶፮ እንዲሁ ፡ ሰባ ፡ ወንድሞቹን ፡ በመግደል ፡ አቤሜሌክ ፡ በአባቱ ፡ ላይ ፡ ያደረገውን ፡ ክፋት ፡ እግዚአብሔር ፡ መለሰበት ። ፶፯ እግዚአብሔርም ፡ የሴኬምን ፡ ሰዎች ፡ ክፋት ፡ ሁሉ ፡ በራሳቸው ፡ ላይ ፡ መለሰባቸው ፤ የይሩበአልም ፡ ልጅ ፡ የኢዮአታም ፡ እርግማን ፡ ደረሰባቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ ከአቤሜሌክም ፡ በኋላ ፡ ከይሳኮር ፡ ነገድ ፡ የሆነ ፡ የዱዲ ፡ ልጅ ፡ የፉሐ ፡ ልጅ ፡ ቶላ ፡ እስራኤልን ፡ ለማዳን ፡ ተነሣ ፤ በተራራማውም ፡ በኤፍሬም ፡ አገር ፡ ባለችው ፡ በሳምር ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ። ፪ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ሀያ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ፈረደ ፤ ሞተም ፥ በሳምርም ፡ ተቀበረ ።

፫ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ገለዓዳዊው ፡ ኢያዕር ፡ ተነሣ ፥ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ሀያ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ፈረደ ። ፬ በሠላሳ ፡ የአህያ ፡ ግልገሎች ፡ ይቀመጡ ፡ የነበሩ ፡ ሠላሳ ፡ ልጆችም ፡ ነበሩት ፤ ለእነርሱም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ የኢያዕር ፡ መንደሮች ፡ የተባሉ ፡ በገለዓድ ፡ ምድር ፡ ያሉ ፡ ሠላሳ ፡ ከተሞች ፡ ነበሩአቸው ። ፭ ኢያዕርም ፡ ሞተ ፥ በቃሞንም ፡ ተቀበረ ።

፮ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ሠሩ ፤ በአሊምንና ፡ አስታሮትን ፡ የሶርያንም ፡ አማልክት ፥ የሲዶናንም ፡ አማልክት ፥ የሞዓብንም ፡ አማልክት ፥ የአሞንንም ፡ ልጆች ፡ አማልክት ፥ የፍልስጥኤማውያንንም ፡ አማልክት ፡ አመለኩ ፤ እግዚአብሔርንም ፡ ተዉ ፥ አላመለኩትምም ። ፯ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ነደደ ፥ በፍልስጥኤማውያንና ፡ በአሞን ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ። ፰ በዚያም ፡ ዓመት ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ሥቃይ ፡ አበዙባቸው ፤ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በአሞራውያን ፡ አገር ፡ በገለዓድ ፡ ውስጥ ፡ ያሉትን ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ አሥራ ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡ ተጋፉአቸው ። ፱ የአሞንም ፡ ልጆች ፡ ከይሁዳ ፡ ከብንያምና ፡ ከኤፍሬም ፡ ቤት ፡ ጋር ፡ ደግሞ ፡ ሊዋጉ ፡ ዮርዳኖስን ፡ ተሻገሩ ፤ እስራኤልም ፡ እጅግ ፡ ተጨነቁ ።

፲ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ — አምላካችንን ፡ ትተን ፡ በአሊምን ፡ አምልከናልና ፡ አንተን ፡ በድለናል ፡ ብለው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ። ፲፩ እግዚአብሔርም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ አላቸው ፡ — ግብፃውያን ፥ አሞራውያንም ፥ የአሞንም ፡ ልጆች ፥ ፍልስጥኤማውያንም ፥ ፲፪ ሲዶናውያንም ፥ አማሌቃውያንም ፥ ማዖናውያንም ፡ አላስጨነቋችሁምን ? ወደ ፡ እኔም ፡ ጮኻችሁ ፥ እኔም ፡ ከእጃቸው ፡ አዳንኋችሁ ። ፲፫ እናንተ ፡ ግን ፡ ተዋችሁኝ ፡ ሌሎችንም ፡ አማልክት ፡ አመለካችሁ ፤ ስለዚህም ፡ ደግሞ ፡ አላድናችሁም ። ፲፬ ሄዳችሁ ፡ የመረጣችኋቸውን ፡ አማልክት ፡ ጥሩ ፤ እነርሱም ፡ በመከራችሁ ፡ ጊዜ ፡ ያድኑአችሁ ። ፲፭ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እግዚአብሔርን ፡ — እኛ ፡ ኃጢአትን ፡ ሠርተናል ፤ አንተ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝህን ፡ አድርግብን ፤ ዛሬ ፡ ግን ፥ እባክህ ፥ አድነን ፡ አሉት ። ፲፮ ሌሎችንም ፡ አማልክት ፡ ከመካከላቸው ፡ አስወገዱ ፥ እግዚአብሔርንም ፡ አመለኩ ፤ ነፍሱም ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡ ጕስቍልና ፡ አዘነች ።

፲፯ የአሞንም ፡ ልጆች ፡ ተሰብስበው ፡ በገለዓድ ፡ ሰፈሩ ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ተሰብስበው ፡ በምጽጳ ፡ ሰፈሩ ። ፲፰ ሕዝቡም ፥ የገለዓድ ፡ አለቆች ፥ እርስ ፡ በእርሳቸው ፡ — ከአሞን ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ መዋጋት ፡ የሚጀምር ፡ ማን ፡ ነው ? እርሱ ፡ በገለዓድ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ ይሆናል ፡ አሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ገለዓዳዊውም ፡ ዮፍታሔ ፡ ጽኑዕ ፡ ኃያል ፡ ሰው ፡ የጋለሞታ ፡ ሴትም ፡ ልጅ ፡ ነበረ ። ገለዓድም ፡ ዮፍታሔን ፡ ወለደ ። ፪ የገለዓድም ፡ ሚስት ፡ ወንዶች ፡ ልጆችን ፡ ወለደችለት ፤ ልጆችዋም ፡ በደጉ ፡ ጊዜ ፡ ዮፍታሔን ፡ — የልዩ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ነህና ፡ በአባታችን ፡ ቤት ፡ አትወርስም ፡ ብለው ፡ አሳደዱት ። ፫ ዮፍታሔም ፡ ከወንድሞቹ ፡ ፊት ፡ ሸሽቶ ፡ በጦብ ፡ ምድር ፡ ተቀመጠ ፤ ምናምንቴዎችም ፡ ሰዎች ፡ ተሰብስበው ፡ ዮፍታሔን ፡ ተከተሉት ።

፬ ከዚያም ፡ ወራት ፡ በኋላ ፡ የአሞን ፡ ልጆች ፡ ከእስራኤል ፡ ጋር ፡ ይዋጉ ፡ ነበር ። ፭ የአሞንም ፡ ልጆች ፡ ከእስራኤል ፡ ጋር ፡ በተዋጉ ፡ ጊዜ ፡ የገለዓድ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ዮፍታሔን ፡ ከጦብ ፡

ምድር ፡ ለማምጣት ፡ ሄዱ ። ፮ ዮፍታሔንም ፡— ና ፡ ከአሞን ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ እንድንዋጋ ፡ አለቃችን ፡ ሁን ፡ አሉት ። ፯ ዮፍታሔም ፡ የገለዓድን ፡ ሽማግሌዎች ፡— የጠላችሁኝ ፡ ከአባቴም ፡ ቤት ፡ ያሳደዳችሁኝ ፡ እናንተ ፡ አይደላችሁምን? አሁን ፡ በተጨነቃችሁ ፡ ጊዜ ፡ ለምን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጣችሁ? አላቸው ። ፰ የገለዓድም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ዮፍታሔን ፡— ከእኛ ፡ ጋር ፡ እንድትወጣ ፡ ከአሞንም ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ እንድትዋጋ ፡ ስለዚህ ፡ አሁን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ተመልሰን ፡ መጣን ፤ በገለዓድም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አለቃችን ፡ ትሆናለህ ፡ አሉት ። ፱ ዮፍታሔም ፡ የገለዓድን ፡ ሽማግሌዎች ፡— ከአሞን ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ ለመዋጋት ፡ ወደ ፡ አገሬ ፡ ብትመልሱኝ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በእጄ ፡ አሳልፎ ፡ ቢሰጣቸው ፡ እኔ ፡ አለቃችሁ ፡ እሆናለሁን? አላቸው ። ፲ የገለዓድም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ዮፍታሔን ፡— እግዚአብሔር ፡ በመካከላችን ፡ ምስክር ፡ ይሁን ፤ በእርግጥ ፡ እንደ ፡ ቃልህ ፡ እናደርጋለን ፡ አሉት ። ፲፩ ዮፍታሔም ፡ ከገለዓድ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ጋር ፡ ሄደ ፡ ሕዝቡም ፡ በላያቸው ፡ ራስና ፡ አለቃ ፡ አደረጉት ፤ ዮፍታሔም ፡ ቃሉን ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በምጽጳ ፡ ተናገረ ።

፲፪ ዮፍታሔም ፡ ወደ ፡ አሞን ፡ ልጆች ፡ ንጉሥ ፡— አገሬን ፡ ለመውጋት ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ የምትመጣ ፡ አንተ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አለህ? ብሎ ፡ መልክተኞችን ፡ ላከ ። ፲፫ የአሞንም ፡ ልጆች ፡ ንጉሥ ፡ የዮፍታሔን ፡ መልክተኞች ፡— እስራኤል ፡ ከግብፅ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ከአርኖን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ያቦቅና ፡ እስከ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ድረስ ፡ ምድሬን ፡ ስለ ፡ ወሰደ ፡ ነው ፤ አሁንም ፡ በሰላም ፡ መልሱልኝ ፡ ብሎ ፡ መለሰላቸው ። ፲፬ ዮፍታሔም ፡ ወደ ፡ አሞን ፡ ልጆች ፡ ንጉሥ ፡ መልክተኞችን ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ላከ ፡ እንዲህም ፡ አለው ፡— ፲፭ ዮፍታሔ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እስራኤል ፡ የሞዓብን ፡ ምድር ፡ የአሞንንም ፡ ልጆች ፡ ምድር ፡ አልወሰደም ፤ ፲፮ ነገር ፡ ግን ፡ ከግብፅ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ እስራኤልም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ኤርትራ ፡ ባሕር ፡ በሄደ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ቃዴስም ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ፲፯ እስራኤል ፡ ወደ ፡ ኤዶምያስ ፡ ንጉሥ ፡— በምድርህ ፡ እንዳልፍ ፡ እባክህ ፡ ፍቀድልኝ ፡ ብሎ ፡ መልክተኞችን ፡ ላከ ፤ የኤዶምያስም ፡ ንጉሥ ፡ አልሰማም ። እንዲሁም ፡ ወደ ፡ ሞዓብ ፡ ንጉሥ ፡ ላከ ፡ እርሱም ፡ አልፈቀደም ። እስራኤልም ፡ በቃዴስ ፡ ተቀመጠ ። ፲፰ በምድረ ፡ በዳም ፡ በኩል ፡ ሄዱ ፡ የኤዶምያስንና ፡ የሞዓብንም ፡ ምድር ፡ ዞሩ ፤ ከሞዓብ ፡ ምድርም ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ መጡ ፡ በአርኖንም ፡ ማዶ ፡ ሰፈሩ ፤ አርኖንም ፡ የሞዓብ ፡ ድንበር ፡ ነበረና ፡ የሞዓብን ፡ ድንበር ፡ አላለፉም ። ፲፱ እስራኤልም ፡ ወደ ፡ አሞራዊው ፡ ወደ ፡ ሐሴቦን ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ሴዎን ፡ መልክተኞችን ፡ ላከ ፤ እስራኤልም ፡— በምድርህ ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ስፍራችን ፡ እባክህ ፡ አሳልፈን ፡ አለው ። ፳ ሴዎንም ፡ እስራኤል ፡ በድንበሩ ፡ እንዲያልፍ ፡ አላመነውም ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሴዎን ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰበ ፡ በያሀጽም ፡ ሰፈረ ፡ ከእስራኤልም ፡ ጋር ፡ ተዋጋ ። ፳፩ የእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሴዎንንና ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ በእስራኤል ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠ ፡ መቱአቸውም ፤ እስራኤልም ፡ በዚያ ፡ ምድር ፡ ተቀምጠው ፡ የነበሩትን ፡ የአሞራውያንን ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ወረሰ ። ፳፪ ከአርኖንም ፡ እስከ ፡ ያቦቅ ፡ ድረስ ፡ ከምድረ ፡ በዳውም ፡ እስከ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ድረስ ፡ የአሞራውያንን ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ወረሱ ። ፳፫ የእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሕዝቡ ፡ ከእስራኤል ፡ ፊት ፡ አሞራውያንን ፡ አስወገደ ፤ አንተም ፡ ምድሩን ፡ ትወርሳለህን? ፳፬ አምላክህ ፡ ከሞሽ ፡ የሚሰጥህን ፡ አትወርስምን? እኛም ፡ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ከፊታችን ፡ ያስወጣቸውን ፡ የእነርሱን ፡ ምድር ፡ እንወርሳለን ። ፳፭ ወይስ ፡ ከሞዓብ ፡ ንጉሥ ፡ ከሴፎር ፡ ልጅ ፡ ከባላቅ ፡ አንተ ፡ ትሻላለህን? በውኑ ፡ እርሱ ፡ እስራኤልን ፡ ከቶ ፡ ተጣላውን? ወይስ ፡ ተዋጋውን? ፳፮ እስራኤልም ፡ በሐሴቦንና ፡ በመንደሮችዋ ፡ በአሮዔርና ፡ በመንደሮችዋ ፡ በአርኖንም ፡ አቅራቢያ ፡ ባሉት ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ዓመት ፡ ተቀምጦ ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፡ በዚያ ፡ ዘመን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አልወሰዳችኋቸውም ፡ ነበር? ፳፯ እኔ ፡ አልበደልሁህም ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ እየተዋጋህ ፡ በድለኸኛል ፤ ፈራጁ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእስራኤል ፡ ልጆችና ፡ በአሞን ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ዛሬ ፡ ይፍረድ ። ፳፰ ነገር ፡ ግን ፡ ዮፍታሔ ፡ የላከበትን ፡ ቃል ፡ የአሞን ፡ ልጆች ፡ ንጉሥ ፡ አልሰማም ።

፳፱ የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በዮፍታሔ ፡ ላይ ፡ መጣ ፤ እርሱም ፡ ገለዓድንና ፡ ምናሴን ፡ አለፈ ፡ በገለዓድም ፡ ያለውን ፡ ምጽጳን ፡ አለፈ ፡ ከምጽጳም ፡ ወደ ፡ አሞን ፡ ልጆች ፡ አለፈ ። ፴ ዮፍታሔም ፡— በእውነት ፡ የአሞንን ፡ ልጆች ፡ በእጄ ፡ አሳልፈህ ፡ ብትሰጠኝ ፡ ፴፩ ከአሞን ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ በደኅና ፡ በተመለስሁ ፡ ጊዜ ፡ ሊገናኘኝ ፡ ከቤቴ ፡ ደጅ ፡ የሚወጣው ፡ ማንኛውም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይሆናል ፤ ለሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ አቀርበዋለሁ ፡ ብሎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስእለት ፡ ተሳለ ። ፴፪ ዮፍታሔም ፡ ሊዋጋቸው ፡ ወደ ፡ አሞን ፡ ልጆች ፡ አለፈ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በእጁ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ። ፴፫ ከአሮዔርም ፡ እስከ ፡ ሚኒትና ፡ እስከ ፡ አቤልክራሚም ፡ ድረስ ፡ ሀያ ፡ ከተሞችን ፡ በታላቅ ፡ አገዳደል ፡ መታቸው ። የአሞንም ፡ ልጆች ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ተዋረዱ ።

፴፬ ዮፍታሔም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ወደ ፡ ምጽጳ ፡ መጣ ፡ እነሆም ፡ ልጁ ፡ ከበሮ ፡ ይዛ ፡ እየዘፈነች ፡ ልትገናኘው ፡ ወጣች ፤ ለእርሱም ፡ አንዲት ፡ ብቻ ፡ ነበረች ፤ ከእርስዋም ፡ በቀር ፡ ወንድ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ሌላ ፡ ልጅ ፡ አልነበረውም ። ፴፭ እርስዋንም ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ልብሱን ፡ ቀድዶ ፡— አወይ ፡

ልጄ ፡ ሆይ ! ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አፌን ፡
ከፍቻለሁና ÷ ከዚያውም ፡ እመለስ ፡ ዘንድ ፡ አል
ችልምና ፡ በጣም ፡ አዋረድሽኝ ፡ አስጨነቅሽ
፴፮ ኝም ፡ አላት ። እርስዋም ፡— አባቴ ፡ ሆይ ÷ አፍ
ህን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ከከፈትህ ÷ እግዚአብ
ሔር ፡ በጠላቶችህ ፡ በአሞን ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡
ተበቅሎልሃልና ፡ በአፍህ ፡ እንደ ፡ ተናገርህ ፡
፴፯ አድርግብኝ ፡ አለችው ። አባትዋንም ፡— ይህ ፡
ነገር ፡ ይደረግልኝ ፡ ከዚህ ፡ ሄጄ ፡ በተራሮች ፡
ላይ ፡ እንድወጣና ፡ እንድወርድ ÷ ከባልንጀሮ
ቼም ፡ ጋር ፡ ለድንግልናዬ ፡ እንዳለቅስ ፡ ሁለት ፡
፴፰ ወር ፡ አሰናብተኝ ፡ አለችው ። እርሱም ፡—
ሂጂ ፡ አለ ። ሁለት ፡ ወርም ፡ አሰናበታት ፤ ከባ
ልንጀሮችዋም ፡ ጋር ፡ ሄደች ÷ በተራሮችም ፡
፴፱ ላይ ፡ ለድንግልናዋ ፡ አለቀሰች ። ሁለትም ፡
ወር ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ አባትዋ ፡ ተመ
ለሰች ÷ እንደ ፡ ተሳለውም ፡ ስእለት ፡ አደረገ
ባት ፤ እርስዋም ፡ ወንድ ፡ አላወቀችም ፡ ነበር ።
፵ የእስራኤልም ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ በዓመት ፡ በዓ
መቱ ፡ እየሄዱ ፡ የገለዓዳዊውን ፡ የዮፍታሔን ፡
ልጅ ፡ በዓመት ፡ አራት ፡ ቀን ፡ ሙሾ ፡ እንዲያ
ወጡ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ልማድ ፡ ሆነ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ የኤፍሬም ፡ ሰዎች ፡ ተሰበሰቡ ÷ ወደ ፡ ጻፎ
ንም ፡ ተሻግረው ፡ ዮፍታሔን ፡— ከአሞን ፡
ልጆች ፡ ጋር ፡ ለመዋጋት ፡ ስታልፍ ፡ ከአንተ ፡
ጋር ፡ እንድንሄድ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አልጠራኸንም ?
ቤትህን ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ በእሳት ፡ እናቃጥለዋ
፪ ለን ፡ አሉት ። ዮፍታሔም ፡— ከአሞን ፡ ልጆች ፡
ጋር ፡ ለእኔና ፡ ለሕዝቤ ፡ጽኑ ፡ ጠብ ፡ ነበረን ፤
በጠራኋችሁም ፡ ጊዜ ፡ ከእጃቸው ፡ አላዳናች
፫ ሁኝም ። እንዳላዳናችሁኝም ፡ በየሁ ፡ ጊዜ ፡
ነፍሴን ፡ በእጄ ፡ አድርጌ ፡ በአሞን ፡ ልጆች ፡
ላይ ፡ አለፍሁ ÷ እግዚአብሔርም ፡ በእጄ ፡ አሳ
ልፎ ፡ ሰጣቸው ፤ ለምንስ ፡ ዛሬ ፡ ልትወጉኝ ፡
፬ ወደ ፡ እኔ ፡ መጣችሁ ? አላቸው ። ዮፍታሔም ፡
የገለዓድን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰበ ÷ ከኤፍሬ
ምም ፡ ጋር ፡ ተዋጋ ፤ ኤፍሬምም ፡— ገለዓዳው
ያን ፡ ሆይ ÷ እናንተ ፡ በኤፍሬምና ፡ በምናሴ ፡
መካከል ፡ የተቀመጣችሁት ፡ ከኤፍሬም ፡ ሸሽ
ታችሁ ፡ ነው ፡ ስላሉ ፡ የገለዓድ ፡ ሰዎች ፡ ኤፍሬ
፭ ምን ፡ መቱ ። ገለዓዳውያንም ፡ ኤፍሬም ፡ የሚ
ያልፍበትን ፡ የዮርዳኖስን ፡ መሻገርያ ፡ ያዙብ
ቸው ፤ የሸሸም ፡ የኤፍሬም ፡ ሰው ፡— ልለፍ ፡
ባለ ፡ ጊዜ ÷ የገለዓድ ፡ ሰዎች ፡— አንተ ፡ ኤፍ
ሬማዊ ፡ ነህን ? አሉት ፤ እርሱም ፡— አይደለ
፮ ሁም ፡ ቢል ÷ እነርሱ ፡— እሁን ፡ ሺቦሌት ፡ በል ፡
አሉት ፤ እርሱም ፡ አጥርቶ ፡ መናገር ፡ አልቻ
ለምና ፡— ሲበሌት ፡ አለ ፤ ይዘውም ፡ በዮርዳ
ኖስ ፡ መሻገርያ ፡ አረዱት ፤ በዚያም ፡ ጊዜ ፡ ከኤ
ፍሬም ፡ አርባ ፡ ሁለት ፡ ሺ.ህ ፡ ሰዎች ፡ ወደቁ ።
፯ ዮፍታሔም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ስድስት ፡
ዓመት ፡ ፈረደ ። ገለዓዳዊውም ፡ ዮፍታሔ ፡
ሞተ ÷ ከገለዓድም ፡ ከተሞች ፡ በአንዲቱ ፡ ተቀ
በረ ።

፰ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ የቤተ ፡ ልሔሙ ፡ ኢብ
፱ ጻን ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ፈራጅ ፡ ሆነ ። ሠላ
ሳም ፡ ወንዶች ፡ ልጆችና ፡ ሠላሳ ፡ ሴቶች ፡
ልጆች ፡ ነበሩት ፤ ሠላሳ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቹንም ፡
ወደ ፡ ውጭ ፡ አገር ፡ ዳረ ፤ ለወንዶች ፡ ልጆቹም ፡
ከውጭ ፡ አገር ፡ ሴቶች ፡ ልጆችን ፡ አመጣ ።
በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ፈረደ ።
፲ ኢብጻንም ፡ ሞተ ÷ በቤተ ፡ ልሔምም ፡ ተቀ
በረ ።

፲፩ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ዛብሎናዊው ፡ ኤሎም ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ፈራጅ ፡ ሆነ ፤ እርሱም ፡ በእ
፲፪ ስራኤል ፡ ላይ ፡ አሥር ፡ ዓመት ፡ ፈረደ ። ዛብ
ሎናዊውም ፡ ኤሎም ፡ ሞተ ÷ በዛብሎንም ፡
ምድር ፡ በለችው ፡ በኤሎም ፡ ተቀበረ ።

፲፫ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ የጲርዓቶናዊው ፡ የሂሌል ፡
ልጅ ፡ ዓብዶን ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ፈራጅ ፡ ሆነ ።
፲፬ አርባም ፡ ልጆች ፡ ሠላሳም ፡ የልጅ ፡ ልጆች ፡
ነበሩት ፤ በሰባም ፡ አህያ ፡ ግልገሎች ፡ ላይ ፡ ይቀ
መጡ ፡ ነበር ። በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ስምንት ፡
፲፭ ዓመት ፡ ፈረደ ። የጲርዓቶናዊውም ፡ የሂሌል ፡
ልጅ ፡ ዓብዶን ፡ ሞተ ÷ በተራራማውም ፡ በአማ
ሌቃውያን ፡ ምድር ፡ በኤፍሬም ፡ በለችው ፡ በጲ
ርዓቶን ፡ ተቀበረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ሠሩ ፤ እግዚ
አብሔርም ፡ በፍልስጥኤማውያን ፡ እጅ ፡ አርባ ፡
ዓመት ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ።

፪ ከዳን ፡ ወገን ፡ የሆነ ፡ ማኑሄ ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡
የጾርዓ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ሚስቱም ፡ መካን ፡ ነበ
፫ ረች ÷ ልጅም ፡ አልወለደችም ። የእግዚአብ
ሔርም ፡ መልአክ ፡ ለሴቲቱ ፡ ተገለጠ ፡ እንዲህ ፡
አላት ፡— እነሆ ÷ አንቺ ፡ መካን ፡ ነሽ ÷ ልጅም ፡
አልወለድሽም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ትፀንሻለሽ ÷ ወንድ ፡
፬ ልጅም ፡ ትወልጃለሽ ። አሁንም ፡ ተጠንቀቂ ፤
የወይን ፡ ጠጅን ፡ የሚያሰክርም ፡ ነገር ፡ አት
፭ ጠጪ ÷ ርኩስም ፡ ነገር ፡ አትብዪ ። እነሆ ÷
ትፀንሻለሽ ÷ ወንድ ፡ ልጅም ፡ ትወልጃለሽ ፤
ልጁም ፡ ከእናቱ ፡ ማኅፀን ፡ ጀምሮ ፡ ለእግዚአ
ብሔር ፡ የተለየ ፡ ናዝራዊ ፡ ይሆናልና ፡ በራሱ ፡
ላይ ፡ ምላጭ ፡ አይድረስበት ፤ እርሱም ፡ እስ
ራኤልን ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ እጅ ፡ ማዳን ፡
፮ ይጀምራል ። ሴቲቱም ፡ ወደ ፡ ባልዋ ፡ መጥታ ፡—
አንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጣ ÷
መልኩም ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡
እጅግ ፡ የሚያስደነግጥ ፡ ነበረ ፤ ከወዴትም ፡
እንደ ፡ መጣ ፡ አልጠየቅሁትም ÷ እርሱም ፡
፯ ስሙን ፡ አልነገረኝም ። እርሱም ፡— እነሆ ÷
ትፀንሻለሽ ÷ ወንድ ፡ ልጅም ፡ ትወልጃለሽ ፤
ልጁም ፡ ከእናቱ ፡ ማኅፀን ፡ ጀምሮ ፡ እስኪሞት ፡
ድረስ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተለየ ፡ ናዝራዊ ፡

ይሆናልና ፡ አሁን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ የሚያሰክር ም ፡ ነገር ፡ አትጠጪ ፥ ርኩስም ፡ ነገር ፡ አትብዪ ፡ አለኝ ፡ ብላ ፡ ተናገረች ።

፰፤ ማኑሄም ፡ — ጌታ ፡ ሆይ ፥ የላክኸው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፥ እባክህ ፥ እንደ ፡ ገና ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ ይምጣ ፤ ለሚወለደውም ፡ ልጅ ፡ ምን ፡ እንድናደርግ ፡ ያስገንዝበን ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለመነ ። ፱፤ እግዚአብሔርም ፡ የማኑሄን ፡ ድምፅ ፡ ሰማ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ለሴቲቱ ፡ በእርሻ ፡ ውስጥ ፡ ተቀምጣ ፡ ሳለች ፡ ተገለጠላት ፤ ባልዋ ፡ ማኑሄ ፡ ግን ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ አልነበረም ። ፲፤ ሴቲቱም ፡ ፈጥና ፡ ሮጠች ፡ ለባልዋም ፡ — እነሆ ፥ በቀደም ፡ ዕለት ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ የመጣው ፡ ሰው ፡ ደግሞ ፡ ተገለጠልኝ ፡ ብላ ፡ ነገረችው ። ፲፩፤ ማኑሄም ፡ ተነሥቶ ፡ ሚስቱን ፡ ተከተለ ፥ ወደ ፡ ሰውዮውም ፡ መጥቶ ፡ — ከዚህች ፡ ሴት ፡ ጋር ፡ የተነጋገርህ ፡ አንተ ፡ ነህን ? አለው ። እርሱም ፡ — እኔ ፡ ነኝ ፡ አለ ። ፲፪፤ ማኑሄም ፡ — ቃልህ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ የልጁ ፡ ሥርዓት ፡ ምንድር ፡ ነው ? የምናደርግለትስ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለው ። ፲፫፤ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ማኑሄን ፡ — ሴቲቱ ፡ ከነገርኋት ፡ ሁሉ ፡ ትጠንቀቅ ። ፲፬፤ ከወይንም ፡ ከሚወጣው ፡ ሁሉ ፡ አትብላ ፥ የወይን ፡ ጠጅንም ፡ የሚያሰክርንም ፡ ነገር ፡ አትጠጣ ፥ ርኩስም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አትብላ ፤ ያዘዝኋትን ፡ ሁሉ ፡ ትጠብቅ ፡ አለው ።

፲፭፤ ማኑሄም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መልአክ ፡ — የፍየል ፡ ጠቦት ፡ እስክናዘጋጅልህ ፡ ድረስ ፥ እባክህ ፥ ቆይ ፡ አለው ። ፲፮፤ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ማኑሄን ፡ — አንተ ፡ የግድ ፡ ብትለኝ ፡ መብልህን ፡ አልበላም ፤ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ ማዘጋጀት ፡ ብትወድድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አቅርበው ፡ አለው ። ማኑሄም ፡ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ መሆኑን ፡ አላወቀም ፡ ነበር ። ፲፯፤ ማኑሄም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መልአክ ፡ — ነገርህ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ እንድናከብርህ ፡ ስምህ ፡ ማን ፡ ነው ? አለው ። ፲፰፤ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ — ስሜ ፡ ድንቅ ፡ ነውና ፡ ለምን ፡ ትጠይቃለህ ? አለው ። ፲፱፤ ማኑሄም ፡ የፍየሉን ፡ ጠቦትና ፡ የእህሉን ፡ ቍርባን ፡ወስዶ ፡ በድንጋይ ፡ ላይ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አቀረበው ። መልአኩም ፡ ተአምራት ፡ አደረገ ፥ ማኑሄና ፡ ሚስቱም ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ። ፳፤ ነበልባሉም ፡ ከመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ በመሠዊያው ፡ ነበልባል ፡ ውስጥ ፡ ዐረገ ፤ ማኑሄና ፡ ሚስቱም ፡ ተመለከቱ ፥ በምድርም ፡ በግምባራቸው ፡ ተደፉ ።

፳፩፤ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ዳግመኛ ፡ ለማኑሄና ፡ ለሚስቱ ፡ አልተገለጠም ፤ ያን ፡ ጊዜም ፡ ማኑሄ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ መሆኑን ፡ አወቀ ። ፳፪፤ ማኑሄም ፡ ሚስቱን ፡ — እግዚአብሔርን ፡ አይተናልና ፡ ሞት ፡ እንሞታለን ፡ አላት ። ፳፫፤ ሚስቱም ፡ — እግዚአብሔርስ ፡ ሊገድለን ፡ ቢወድድ ፡ ኖሮ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የእህሉን ፡ ቍርባን ፡ ከእጃችን ፡ ባልተቀበለን ፥ ይህንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ባላሳየን ፥ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገርም ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ባላስታወቀን ፡ ነበር ፡ አለችው ።

፳፬፤ ሴቲቱም ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፥ ስሙንም ፡ ሶምሶን ፡ ብላ ፡ ጠራችው ፤ ልጁም ፡ አደገ ፡ እግዚአብርሔርም ፡ ባረከው ። ፳፭፤ የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በጾርዓና ፡ በኤሽታኦል ፡ መካከል ፡ ባለው ፡ በዳን ፡ ሰፈር ፡ ውስጥ ፡ ሊያነቃቃው ፡ ጀመረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩፤ ሶምሶንም ፡ ወደ ፡ ተምና ፡ ወረደ ፥ በተምናም ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ ልጆች ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ አየ ። ፪፤ ወጥቶም ፡ ለአባቱና ፡ ለእናቱ ፡ — በተምና ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ ልጆች ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ አይቻለሁ ፤ አሁንም ፡ እርስዋን ፡ አጋቡኝ ፡ አላቸው ። ፫፤ አባቱና ፡ እናቱም ፡ — ካልተገረዙት ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ ሚስት ፡ ለማግባት ፡ ትሄድ ፡ ዘንድ ፡ ከወንድሞችህ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ከሕዝቤም ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ ሴት ፡ የለምን ? አሉት ። ሶምሶንም ፡ አባቱን ፡ — ለዓይኔ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አሰኝታኛለችና ፡ እርስዋን ፡ አጋባኝ ፡ አለው ። ፬፤ እግዚአብሔርም ፡ በፍልስጥኤማውያን ፡ ላይ ፡ ምክንያት ፡ ይፈልግ ፡ ነበርና ፡ ነገሩ ፡ ከእርሱ ፡ ሆነ ፤ አባቱና ፡ እናቱ ፡ ግን ፡ አላወቁም ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ገዦች ፡ ነበሩ ።

፭፤ ሶምሶንም ፡ አባቱና ፡ እናቱም ፡ ወደ ፡ ተምና ፡ ወረዱ ፥ በተምናም ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ ወይኑ ፡ ስፍራ ፡ መጡ ፤ እነሆም ፥ የአንበሳ ፡ ደቦል ፡ እያገሣ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ደረሰ ። ፮፤ የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ በኃይል ፡ ወረደ ፤ ጠቦትን ፡ እንደሚቈራርጥ ፡ በእጁ ፡ ምንም ፡ ሳይኖር ፡ ቈራረጠው ፤ ያደረገውንም ፡ ለአባቱና ፡ ለእናቱ ፡ አልነገረም ። ፯፤ ወርዶም ፡ ከሴቲቱ ፡ ጋር ፡ ተነጋገረ ፤ እጅግም ፡ ደስ ፡ አሰኘችው ። ፰፤ ከጥቂትም ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ሊያገባት ፡ ተመለሰ ፥ የአንበሳውንም ፡ ሬሳ ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ ከመንገድ ፡ ፈቀቅ ፡ አለ ፤ እነሆም ፥ በአንበሳው ፡ ሬሳ ፡ ውስጥ ፡ ንብ ፡ ሰፍሮበት ፡ ነበር ፥ ማርም ፡ ነበረበት ። ፱፤ በእጁም ፡ ወስዶ ፡ መንገድ ፡ ለመንገድ ፡ እየበላ ፡ ሄደ ፤ ወደ ፡ አባቱና ፡ ወደ ፡ እናቱ ፡ መጣ ፥ ማሩንም ፡ ሰጣቸው ፥ እነርሱም ፡ በሉ ፤ ማሩንም ፡ ከአንበሳው ፡ ሬሳ ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ ወሰደ ፡ አልነገራቸውም ።

፲፤ አባቱም ፡ ወደ ፡ ሴቲቱ ፡ ወረደ ፤ ጎበዞችም ፡ እንዲህ ፡ ያደርጉ ፡ ነበርና ፡ ሶምሶን ፡ በዚያ ፡ በዓል ፡ አደረገ ። ፲፩፤ ባዩትም ፡ ጊዜ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ሌሎች ፡ ሠላሳ ፡ ሰዎች ፡ ሰጡት ። ፲፪፤ ሶምሶንም ፡ — እንቈቅልሽ ፡ ልስጣችሁ ፤ በሰባቱም ፡ በበዓሉ ፡ ቀኖች ፡ ውስጥ ፡ ፈትታችሁ ፡ ብትነግሩኝ ፥ ሠላሳ ፡ የበፍታ ፡ ቀሚስና ፡ ሠላሳ ፡ ልውጥ ፡ ልብስ ፡ እሰጣችኋለሁ ፤ መፍታትም ፡ ፲፫፤

ባትችሉ ፡ ሠላሳ ፡ የበፍታ ፡ ቀሚስና ፡ ሠላሳ ፡
ልውጥ ፡ ልብስ ፡ ትሰጡኛላችሁ ፡ አላቸው ።
እነርሱም ፡— እንድንሰማው ፡ እንቈቅልሽህን ፡
፲፬ ንገረን ፡ አሉት ። እርሱም ፡— ከበላተኛ ፡ ውስጥ ፡
መብል ፡ ወጣ ÷ ከብርቱም ፡ ውስጥ ፡ ጣፋጭ ፡
ወጣ ፡ አላቸው ። ሦስት ፡ ቀንም ፡ እንቈቅልሹን ፡
መተርጐም ፡ አልቻሉም ።

፲፭ በአራተኛውም ፡ ቀን ፡ የሶምሶንን ፡ ሚስት ፡—
እንቈቅልሹን ፡ እንዲነግረን ፡ ባልሽን ፡ ሸንግ
ዪው ÷ አለዚያም ፡ አንቺንና ፡ የአባትሽን ፡ ቤት ፡
በእሳት ፡ እናቃጥላለን ፤ ወደዚህ ፡ ጠራችሁን ፡
፲፮ ልትገፉን ፡ ነውን ? አሉአት ። የሶምሶንም ፡
ሚስት ፡ በፊቱ ፡ እያለቀሰች ፡— በእውነት ፡ ጠል
ተኸኛል ÷ ከቶም ፡ አትወድደኝም ፤ ለሕዝቤ ፡
ልጆች ፡ እንቈቅልሽ ፡ ሰጥተሃቸዋልና ፡ ትርጓሚ
ውንም ፡ አልነገርኸኝም ፡ አለችው ። እርሱም ፡—
እነሆ ÷ ለአባቴና ፡ ለእናቴ ፡ አልነገርኋቸውም ÷
፲፯ ለአንቺ ፡ እነግርሻለሁን ? አላት ። ሰባቱንም ፡ የበ
ዓል ፡ ቀን ፡ በፊቱ ፡ አለቀሰች ፤ እርስዋም ፡ ነዝ
ንዛዋለችና ፡ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ነገራት ። ትር
፲፰ ጓሜውንም ፡ ለሕዝብዋ ፡ ልጆች ፡ ነገረች ። በሰ
ባተኛውም ፡ ቀን ፡ ፀሐይ ፡ ሳትገባ ፡ የከተማይቱ ፡
ሰዎች ፡— ከማር ፡ የሚጣፍጥ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
ከአንበሳስ ፡ የሚበረታ ፡ ማን ፡ ነው ? አሉት ።
እርሱም ፡— በጊደሬ ፡ ባላረሳችሁ ፡ የእንቈቅል
ሼን ፡ ትርጓሜ ፡ ባላወቃችሁ ፡ ነበር ፡ አላቸው ።
፲፱ የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በላዩ ፡ በኃይል ፡
ወረደ ፤ ወደ ፡ አስቀሎናም ፡ ወረደ ÷ ከዚያም ፡
ሠላሳ ፡ ሰዎችን ፡ ገደለ ÷ ልብሳቸውንም ፡ ወስዶ ፡
እንቈቅልሹን ፡ ለፈቱት ፡ ሰዎች ፡ ሰጠ ። ቍጣ
ውም ፡ ነደደ ÷ ወደ ፡ አባቱም ፡ ቤት ፡ ወጣ ።
፳ የሶምሶን ፡ ሚስት ፡ ግን ፡ ከተባበሩት ፡ ከሚዜ
ዎቹ ፡ ለአንደኛው ፡ ሆነች ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በስንዴ ፡ መከር ፡ ጊዜ ፡ ሶም
ሶን ፡ የፍየል ፡ ጠቦት ፡ ይዞ ፡ ሚስቱን ፡ ሊጠ
ይቅ ፡ ሄደና ፡— ወደ ፡ ጫጉላ ፡ ቤት ፡ ወደ ፡
ሚስቴ ፡ ልግባ ፡ አለ ፤ አባትዋ ፡ ግን ፡ እንዳይ
፪ ገባ ፡ ከለከለው ። አባትዋም ፡— ፈጽመህ ፡ የጠ
ላሃት ፡ መስሎኝ ፡ ለሚዜህ ፡ አጋባኋት ፤ ታናሽ ፡
እኅትዋ ፡ ከርስዋ ፡ ይልቅ ፡ የተዋበች ፡ አይደለ
ችምን ? እባክህ ÷ በእርስዋ ፡ ፋንታ ፡ አግባት ፡
፫ አለው ። ሶምሶንም ፡— ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
በፍልስጥኤማውያን ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ባደርግ ፡ እኔ ፡
፬ ንጹሕ ፡ ነኝ ፡ አላቸው ። ሶምሶንም ፡ ሄዶ ፡ ሦስት ፡
መቶ ፡ ቀበሮች ፡ ያዘ ፤ ችቦም ፡ ወስዶ ፡ ሁለት ፡
ሁለቱንም ፡ ቀበሮች ፡ በጅራታቸው ፡ አሰረ ÷
በሁለቱም ፡ ጅራቶች ፡ መካከል ፡ አንድ ፡ ችቦ ፡
፭ አደረገ ። ችቦውንም ፡ አንድዶ ፡ በቆመው ፡
በፍልስጥኤማውያን ፡ እህል ፡ መካከል ፡ ሰደዳ
ቸው ፤ ነዶውንም ፡ የቆመውንም ፡ እህል ፡ ወይ
፮ ኑንም ፡ ወይራውንም ፡ አቃጠለ ። ፍልስጥኤ
ማውያንም ፡— ይህን ፡ ያደረገው ፡ ማን ፡ ነው ?
አሉ ። እነርሱም ፡— ሚስቱን ፡ ወስዶ ፡ ለሚ
ዜው ፡ አጋብቶበታልና ፡ የተምናዊው ፡ አማች ፡
ሶምሶን ፡ ነው ፡ አሉ ። ፍልስጥኤማውያንም ፡
ወጥተው ፡ ሴቲቱንና ፡ አባትዋን ፡ በእሳት ፡ አቃ
፯ ጠሉ ። ሶምሶንም ፡— እናንተ ፡ እንዲሁ ፡ ብታ
ደርጉ ፡ እኔ ፡ እበቀላችኋለሁ ÷ ከዚያም ፡ በኋላ ፡
፰ ዐርፋለሁ ፡ አላቸው ። እርሱም ፡ ጭን ፡ ጭና
ቸውን ፡ ብሎ ፡ በታላቅ ፡ አገዳደል ፡ መታቸው ፡
ወርዶም ፡ በኤጣም ፡ ዓለት ፡ ባለው ፡ ዋሻ ፡
ውስጥ ፡ ተቀመጠ ።

፱ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ወጡ ÷ በይሁዳም ፡
ሰፈሩ ÷ በሌሒ ፡ ላይም ፡ ተበታትነው ፡ ተቀ
፲ መጡ ። የይሁዳም ፡ ሰዎች ፡— በእኛ ፡ ላይ ፡
የወጣችሁት ፡ ለምንድር ፡ ነው ? አሉ ። እነር
ሱም ፡— ሶምሶንን ፡ ልናስር ÷ እንዳደረገብንም ፡
፲፩ ልናደርግበት ፡ መጥተናል ፡ አሉ ። ከይሁዳም ፡
ሰዎች ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ የሚያህሉ ፡ በኤጣም ፡
ዓለት ፡ ወዳለው ፡ ዋሻ ፡ ወርደው ፡ ሶምሶንን ፡—
ገዦቻችን ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡
አታውቅምን ? ያደረግህብን ፡ ይህ ፡ ምንድር ፡
ነው ? አሉት ። እርሱም ፡— እንዳደረጉብኝ ፡ እን
፲፪ ዲሁ ፡ አደረግሁባቸው ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡—
አስረን ፡ በፍልስጥኤማውያን ፡ እጅ ፡ አሳልፈን ፡
ልንሰጥህ ፡ መጥተናል ፡ አሉት ። ሶምሶንም ፡—
እናንተ ፡ እንዳትገድሉኝ ፡ ማሉልኝ ፡ አላቸው ።
፲፫ እነርሱም ፡— አስረን ፡ በእጃቸው ፡ አሳልፈን ፡
እንሰጥሃለን ፡ እንጂ ፡ አንገድልህም ፡ ብለው ፡
ተናገሩት ። በሁለትም ፡ አዲስ ፡ ገመድ ፡ አስ
ረው ፡ ከዓለቱ ፡ ውስጥ ፡ አወጡት ።

፲፬ ወደ ፡ ሌሒ ፡ በመጣ ፡ ጊዜም ፡ ፍልስጥኤማ
ውያን ፡ እልል ፡ እያሉ ፡ ተገናኙት ። የእግዚአ
ብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በኃይል ፡ ወረደበት ፤ ክን
ዱም ፡ የታሰረበት ፡ ገመድ ፡ በእሳት ፡ እንደ ፡
ተበላ ፡ እንደ ፡ ተልባ ፡ እግር ፡ ፈትል ፡ ሆነ ÷
፲፭ ማሰሪያዎቹም ፡ ከእጁ ፡ ወደቁ ። አዲስም ፡ የአ
ህያ ፡ መንጋጋ ፡ አገኘ ÷ እጁንም ፡ ዘርግቶ ፡ ወሰ
ደው ÷ በእርሱም ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ ሰው ፡ ገደለ ።
፲፮ ሶምሶንም ፡— በአህያ ፡ መንጋጋ ፡ ክምር ፡ በክ
ምር ፡ ላይ ፡ አድርጌአቸዋለሁ ፤ በአህያ ፡ መንጋጋ ፡
፲፯ አንድ ፡ ሺህ ፡ ሰው ፡ ገድያለሁ ፡ አለ ። መናገሩ
ንም ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ መንጋጋውን ፡ ከእጁ ፡
ጣለ ፤ የዚያንም ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ ራማትሌሒ ፡ ብሎ ፡
፲፰ ጠራው ። እርሱም ፡ እጅግ ፡ ተጠምቶ ፡ ነበ
ርና ፡— አንተ ፡ ይህችን ፡ ታላቅ ፡ ማዳን ፡ በባሪ
ያህ ፡ እጅ ፡ ሰጥተሃል ፤ አሁንም ፡ በጥም ፡ እሞ
ታለሁ ÷ ባልተገረዙትም ፡ እጅ ፡ እወድቃለሁ ፡
፲፱ ብሎ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኸ ። እግዚአብ
ሔርም ፡ በሌሒ ፡ ያለውን ፡ አዘቅት ፡ ሰነጠቀ ÷
ከእርሱም ፡ ውኃ ፡ ወጣ ፤ እርሱም ፡ ጠጣ ÷
ነፍሱም ፡ ተመለሰች ÷ ተጠናከረም ። ስለዚ
ህም ፡ የዚያን ፡ ቦታ ፡ ስም ፡ ዓይንሀቆሬ ፡ ብሎ ፡
ጠራው ፤ ይህም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በሌሒ ፡
፳ አለ ። በፍልስጥኤማውያንም ፡ ዘመን ፡ በእስ
ራኤል ፡ ላይ ፡ ሀያ ፡ ዓመት ፡ ፈረደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ ሶምሶንም ፡ ወደ ፡ ጋዛ ፡ ሄደ ÷ በዚያም ፡ ጋለ
፪ ሞታ ፡ ሴት ፡ አይቶ ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ገባ ። የጋዛ ፡
ሰዎችም ፡ ሶምሶን ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ውስጥ ፡
እንደ ፡ ገባ ፡ ሰሙ ÷ ከበቡትም ÷ ሌሊቱንም ፡
ሁሉ ፡ በከተማይቱ ፡ በር ፡ ሸመቁበት ፡— ማለዳ ፡
እንገድለዋለን ፡ ብለውም ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ በዝ
፫ ምታ ፡ ተቀመጡ ። ሶምሶንም ፡ እስከ ፡ እኩለ ፡
ሌሊት ፡ ተኛ ፤ እኩለ ፡ ሌሊትም ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡
ተነሥቶ ፡ የከተማይቱን ፡ በር ፡ መዝጊያ ፡ ያዘ ÷
ከሁለቱ ፡ መቃኖችና ፡ ከመወርወሪያውም ፡ ጋር ፡
ነቀለው ÷ በትከሻውም ፡ ላይ ፡ አደረገ ÷ በኬብ
ሮንም ፡ ፊት ፡ ወዳለው ፡ ተራራ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡
ተሸክሞት ፡ ወጣ ፡ በዚያም ፡ ጣለው ።

፬ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በሶሬቅ ፡ ሸለቆ ፡ የነበረች ፡
ደሊላ ፡ የተባለች ፡ አንዲት ፡ ሴትን ፡ ወደደ ።
፭ የፍልስጥኤማውያንም ፡ መኳንንት ፡ ወደ ፡ እር
ስዋ ፡ ወጥተው ፡— እርሱን ፡ሸንግለሽ ፡ በእርሱ ፡
ያለ ፡ ታላቅ ፡ ኃይል ፡ በምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷
እኛስ ፡ እርሱን ፡ ለማዋረድ ፡ እናስረው ፡ ዘንድ ፡
የምናሸንፈው ፡ በምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እወቂ ፤
እኛም ፡ እያንዳንዳችን ፡ ሺህ ፡ አንድ ፡ መቶ ፡
ብር ፡ ሺህ ፡ አንድ ፡ መቶ ፡ ብር ፡ እንሰጥሻለን ፡
፮ አሉአት ። ደሊላም ፡ ሶምሶንን ፡— ታላቅ ፡ ኃይ
ልህ ፡ በምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ እንድትዋረድስ ፡
የምትታሰርበት ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ እባክህ ÷
፯ ንገረኝ ፡ አለችው ። ሶምሶንም ፡— በሰባት ፡
ባልደረቀ ፡ በእርጥብ ፡ ጠፍር ፡ ቢያስሩኝ ÷ እደ
ከማለሁ ፡ እንደ ፡ ሌላም ፡ ሰው ፡ እሆናለሁ ፡
፰ አላት ። የፍልስጥኤማውያንም ፡ መኳንንት ፡
ሰባት ፡ ያልደረቀ ፡ እርጥብ ፡ ጠፍር ፡ አመጡ
፱ ላት ÷ በእርሱም ፡ አሰረችው ። በጓዳዋም ፡
ውስጥ ፡ ሰዎች ፡ ተደብቀው ፡ ነበር ። እርስ
ዋም ፡— ሶምሶን ፡ ሆይ ÷ ፍልስጥኤማውያን ፡
መጡብህ ፡ አለችው ። እርሱም ፡ የተልባ ፡
እግር ፡ ፈትል ፡ እሳት ፡ በሸተተው ፡ ጊዜ ፡ እን
ዲበጠስ ፡ ጠፍሩን ፡ በጣጠሰው ፤ ኃይሉም ፡
በምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አልታወቀም ።

፲ ደሊላም ፡ ሶምሶንን ፡— እነሆ ÷ አታለልኸኝ ÷
የነገርኸኝም ፡ ሐሰት ፡ ነው ፤ አሁንም ፡ የምትታ
ሰርበት ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ እባክህ ÷ ንገረኝ ፡
፲፩ አለችው ። እርሱም ፡— ሥራ ፡ ባልተሠራበት ፡
በአዲስ ፡ ገመድ ፡ ቢያስሩኝ ÷ እደክማለሁ ÷
፲፪ እንደ ፡ ሌላም ፡ ሰው ፡ እሆናለሁ ፡ አላት ። ደሊ
ላም ፡ አዲስ ፡ ገመድ ፡ ወስዳ ፡ በእርሱ ፡ አሰረ
ችው ፤ በጓዳዋም ፡ የተደበቁ ፡ ሰዎች ፡ ተቀም
ጠው ፡ ነበር ። እርስዋም ፡— ሶምሶን ፡ ሆይ ÷
ፍልስጥኤማውያን ፡ መጡብህ ፡ አለችው ። ገመ
ዱንም ፡ ከክንዱ ፡ እንደ ፡ ፈትል ፡ በጣጠሰው ።

፲፫ ደሊላም ፡ ሶምሶንን ፡— እስከ ፡ አሁን ፡ ድረስ ፡
አታለልኸኝ ÷ የነገርኸኝም ፡ ሐሰት ፡ ነው ፤ የምት
ታሰርበት ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ንገረኝ ፡ አለችው ።
እርሱም ፡— የራሴን ፡ ጠጕር ፡ ሰባቱን ፡ ጕንጕን ፡
ከድር ፡ ጋር ፡ ብትጐነጕኚው ÷ በችካልም ፡ ብት
ቸክዪው ÷ እደክማለሁ ÷ እንደ ፡ ሌላም ፡ ሰው ፡
፲፬ እሆናለሁ ፡ አላት ። ሶምሶንም ፡ በተኛ ፡ ጊዜ ፡
ደሊላ ፡ የራሱን ፡ ጠጕር ፡ ሰባቱን ፡ ጕንጕን ፡
ከድሩ ፡ ጋር ፡ ጐነጐነችው ÷ በችካልም ፡ ቸከለ
ችውና ፡— ሶምሶን ፡ ሆይ ÷ ፍልስጥኤማውያን ፡
መጡብህ ፡ አለችው ። ከእንቅልፉም ፡ ነቃ ÷
ችካሉንም ፡ ከነቆንዳላው ፡ ድሩንም ፡ ነቀለ ።
፲፭ እርስዋም ፡— አንተ ፡— እወድድሻለሁ ፡ እን
ዴት ፡ ትለኛለህ ÷ ልብህ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ አይደ
ለም ? ስታታልለኝ ፡ ይህ ፡ ሦስተኛ ፡ ጊዜህ ፡ ነው ÷
ታላቅ ፡ ኃይልህም ፡ በምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አልነ
፲፮ ገርኸኝም ፡ አለችው ። ዕለት ፡ ዕለትም ፡ በቃ
ልዋ ፡ ነዘነዘችው ፡ አስቸገረችውም ÷ ነፍሱም ፡
፲፯ እስከ ፡ ሞት ፡ ድረስ ፡ ተጨነቀች ። እርሱም ፡—
ከእናቴ ፡ ማኅፀን ፡ ጀምሬ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
የተለየሁ ፡ ነኝና ፡ በራሴ ፡ ላይ ፡ ምላጭ ፡ አልደ
ረሰም ፤ የራሴንም ፡ ጠጕር ፡ ብላጭ ፡ ኃይሌ ፡
ከእኔ ፡ ይሄዳል ÷ እደክማለሁም ÷ እንደ ፡ ሌላም ፡
ሰው ፡ እሆናለሁ ፡ ብሎ ፡ የልቡን ፡ ሁሉ ፡ ገለጠ
፲፰ ላት ። ደሊላም ፡ የልቡን ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ገለጠ
ላት ፡ በየች ፡ ጊዜ ፡— የልቡን ፡ ሁሉ ፡ ገልጦል
ኛልና ፡ ይህን ፡ ጊዜ ፡ ደግሞ ፡ ኑ ፡ ብላ ፡ ላከችና ፡
የፍልስጥኤማውያንን ፡ መኳንንት ፡ ጠራች ።
የፍልስጥኤማውያን ፡ መኳንንትም ፡ ብሩን ፡ በእ
፲፱ ጃቸው ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ መጡ ። እር
ስዋም ፡ በጕልበትዋ ፡ ላይ ፡ አስተኛችው ፤ አንድ ፡
ሰውም ፡ ጠራች ÷ እርሱም ፡ ሰባቱን ፡ የራሱን ፡
ጕንጕን ፡ ላጨው ። ልታዋርደውም ፡ ጀመረች ÷
፳ ኃይሉም ፡ ከእርሱ ፡ ሄደ ። እርስዋም ፡— ሶምሶን ፡
ሆይ ÷ ፍልስጥኤማውያን ፡ መጡብህ ፡ አለችው ።
ከእንቅልፉም ፡ ነቅቶ ፡— እወጣለሁ ፡ እንደ ፡ ወት
ሮውም ፡ ጊዜ ፡ አደርጋለሁ ፡ አለ ። ነገር ፡ ግን ፡
እግዚአብሔር ፡ ከእርሱ ፡ እንደ ፡ ተለየው ፡ አላ
፳፩ ወቀም ። ፍልስጥኤማውያንም ፡ ይዘው ፡ ዓይ
ኖቹን ፡ አወጡት ፤ ወደ ፡ ጋዛም ፡ አምጥተው ፡
በናስ ፡ ሰንሰለት ፡ አሰሩት ፤ በግዞትም ፡ ሆኖ ፡
፳፪ እህል ፡ ይፈጭ ፡ ነበር ። የራሱም ፡ ጠጕር ፡ ከላ
ጩት ፡ በኋላ ፡ ያድግ ፡ ጀመር ።

፳፫ የፍልስጥኤምም ፡ መኳንንት ፡— አምላካችን ፡
ጠላታችንን ፡ ሶምሶንን ፡ በእጃችን ፡ አሳልፎ ፡
ሰጠን ፡ እያሉ ፡ ለአምላካቸው ፡ ለዳጎን ፡ ታላቅ ፡
መሥዋዕት ፡ ይሠው ፡ ዘንድ ፡ ደስም ፡ ይላቸው ፡
፳፬ ዘንድ ፡ ተሰበሰቡ ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በዩት ፡
ጊዜ ፡— ምድራችንን ፡ ያጠፋውን ÷ ከእኛም ፡
ብዙ ፡ ሰው ፡ የገደለውን ፡ ጠላታችንን ፡ አምላ
ካችን ፡ በእጃችን ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠን ፡ እያሉ ፡
፳፭ አምላካቸውን ፡ አመሰገኑ ። ልባቸውንም ፡
ደስ ፡ ባለው ፡ ጊዜ ፡— በፊታችን ፡ እንዲጫወት ፡
ሶምሶንን ፡ ጥሩት ፡ አሉ ። ሶምሶንንም ፡ ከግ
ዞት ፡ ቤት ፡ ጠሩት ÷ በፊታቸውም ፡ ተጫወተ ፤
ተዘባበቱበትም ÷ በምሰሶና ፡ በምሰሶም ፡ መካ
፳፮ ከል ፡ አቆሙት ። ሶምሶንም ፡ እጁን ፡ የያዘውን ፡
ብላቴና ፡— ቤቱን ፡ የደገፉትን ፡ ምሰሶች ፡ እጠጋ

በቸው ፡ ዘንድ ÷ እባክህ ÷ አስይዘኝ ፡ አለው ።
፳፯ በቤትም ፡ ውስጥ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ሞልተ
ውበት ፡ ነበር ÷ የፍልስጥኤምም ፡ መኳንንት ፡
ሁሉ ፡ በዚያ ፡ ነበሩ ፤ በቤቱም ፡ ሰገነት ፡ ላይ ፡
ሶምሶን ፡ ሲጫወት ፡ የሚያዩ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ የሚ
ያህሉ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ነበሩ ።
፳፰ ሶምሶንም ፡— ስለ ፡ ሁለቱ ፡ ዓይኖቼ ፡ ፍል
ስጥኤማውያንን ፡ አሁን ፡ እንድበቀል ÷ እግዚ
አብሔር ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ እባክህ ÷ አስበኝ ፤
አምላክ ፡ ሆይ ÷ ይህን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ÷ እባ
ክህ ÷ አበርታኝ ፡ ብሎ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠራ ።
፳፱ ሶምሶንም ፡ ቤቱ ፡ ተደግፎባቸው ፡ የነበሩትን ፡
ሁለቱን ፡ መካከለኞች ፡ ምሰሶች ፡ ያዘ ፤ አንዱን ፡
በቀኝ ፡ እጁ ፡ አንዱንም ፡ በግራ ፡ እጁ ፡ ይዞ ፡
፴ ተጠጋባቸው ። ሶምሶንም ፡— ከፍልስጥኤማው
ያን ፡ ጋር ፡ ልሙት ፡ አለ ፤ ተጎንብሶም ፡ ምሰሶ
ቹን ፡ በሙሉ ፡ ኃይሉ ፡ ገፋ ÷ ቤቱም ፡ በውስጡ ፡
በነበሩት ፡ በመኳንንቱም ፡ በሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ ወደቀ ፤ በሞቱም ፡ የገደላቸው ፡ ሙታን ፡
፴፩ በሕይወት ፡ ሳለ ፡ ከገደላቸው ፡ በዙ ። ወንድሞ
ቹም ፡ የአባቱ ፡ ቤት ፡ ሰቦችም ፡ ሁሉ ፡ ወረዱ ÷
ይዘውም ፡ አመጡት ፤ በጸርዓና ፡ በኤሽታኦል ፡
መካከል ፡ ባለው ፡ በአባቱ ፡ በማኑሄ ፡ መቃብር ፡
ቀበሩት ። እርሱም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ሀያ ፡
ዓመት ፡ ፈረደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ በተራራማውም ፡ በኤፍሬም ፡ አገር ፡ ሚካ ፡
፪ የተባለ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበረ ። እናቱንም ፡—
ከአንቺ ፡ ዘንድ ፡ የተወሰደው ÷ የረገምሽበትም ÷
በጆሮዬም ፡ የተናገርሽበት ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ አንድ ፡
መቶ ፡ ብር ÷ እነሆ ÷ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ አለ ፤ እኔም ፡
ወስጄዋለሁ ፡ አላት ። እናቱም ፡— ልጄ ፡ ሆይ ÷
፫ እግዚአብሔር ፡ ይባርክህ ፡ አለችው ። አንዱን ፡
ሺህ ፡ አንዱን ፡ መቶ ፡ ብርም ፡ መለሰላት ፤ እና
ቱም ፡— ይህን ፡ ብር ፡ የተቀረጸ ፡ ምስልና ፡
ቀልጦ ፡ የተሠራ ፡ ምስል ፡ አድርጌ ፡ ከእጄ ፡ ስለ ፡
ልጄ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እቀድሰዋለሁ ፤ አሁ
፬ ንም ፡ ለአንተ ፡ እመልሰዋለሁ ፡ አለች ። ለእና
ቱም ፡ ገንዘቡን ፡ በመለሰላት ፡ ጊዜ ፡ እናቱ ፡
ሁለቱን ፡ መቶ ፡ ብር ፡ ወስዳ ፡ ለአንጥረኛ ፡ ሰጠ
ችው ÷ እርሱም ፡ የተቀረጸ ፡ ምስልና ፡ ቀልጦ ፡
የተሠራ ፡ ምስል ፡ አደረገው ። ያም ፡ በሚካ ፡
፭ ቤት ፡ ነበረ ። ሰውዮውም ፡ ሚካ ፡ የአምላክ ፡
ቤት ፡ ነበረው ፤ ኤፉድና ፡ ተራፊም ፡ አደረገ ÷
ከልጆቹም ፡ አንዱን ፡ ቀደሰው ÷ ካህንም ፡ ሆነ
፮ ለት ። በዚያም ፡ ዘመን ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡
ንጉሥ ፡ አልነበረም ፤ ሰውም ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡
መልካም ፡ መስሎ ፡ የታየውን ፡ ያደርግ ፡ ነበር ።
፯ በቤተ ፡ ልሔም ፡ ይሁዳም ፡ ከይሁዳ ፡ ወገን ፡
የሆነ ፡ አንድ ፡ ጐልማሳ ፡ ነበረ ÷ እርሱም ፡ ሌዋዊ ፡
፰ ነበረ ÷ በዚያም ፡ ይቀመጥ ፡ ነበር ። ይህም ፡
ሰው ፡ የሚቀመጥበትን ፡ ስፍራ ፡ ለመሻት ፡ ከከ
ተማው ፡ ከቤተ ፡ ልሔም ፡ ይሁዳ ፡ ወጣ ፤ ሲሔ
ድም ፡ ወደ ፡ ተራራማው ፡ ወደ ፡ ኤፍሬም ፡ አገር ፡
፱ ወደ ፡ ሚካ ፡ ቤት ፡ መጣ ። ሚካም ፡— ከወዴት ፡
መጣህ ? አለው ። እርሱም ፡— ከቤተ ፡ ልሔም ፡
ይሁዳ ፡ የሆንሁ ፡ ሌዋዊ ፡ ነኝ ፤ የምቀመጥበት
ንም ፡ ስፍራ ፡ ለመሻት ፡ እሄዳለሁ ፡ አለው ።
፲ ሚካም ፡— ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ተቀመጥ ÷ አባትና ፡
ካህንም ፡ ሁነኝ ፤ እኔም ፡ ልብሶችንና ፡ ምግብ
ህን ÷ በየዓመቱም ፡ አሥር ፡ ብር ፡ እሰጥሃለሁ ፡
፲፩ አለው ። ሌዋዊውም ፡ ገባ ። ሌዋዊውም ፡ ከሰ
ውዮው ፡ ጋር ፡ መቀመጥን ፡ ፈቀደ ፤ ጐልማሳ
ውም ፡ ከልጆቹ ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ሆነለት ።
፲፪ ሚካም ፡ ሌዋዊውን ፡ ቀደሰ ÷ ጐልማሳውም ፡
ካህኑ ፡ ሆነለት ÷ በሚካም ፡ ቤት ፡ ነበረ ።
፲፫ ሚካም ፡— ሌዋዊ ፡ ካህን ፡ ስለ ፡ ሆነልኝ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ መልካም ፡ እንዲሠራልኝ ፡ አሁን ፡
አውቃለሁ ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ በዚያም ፡ ዘመን ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ንጉሥ ፡
አልነበረም ። እስከዚያም ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ለዳን ፡
ነገድ ፡ በእስራኤል ፡ ነገዶች ፡ መካከል ፡ ርስት ፡
አልደረሳቸውም ፡ ነበርና ፡ በዚያ ፡ ዘመን ፡ የሚ
፪ ቀመጡበት ፡ ርስት ፡ ይሹ ፡ ነበር ። የዳንም ፡
ልጆች ፡ ከወገናቸው ፡ አምስት ፡ ጽኑዓን ፡ ሰዎች ፡
ምድሪቱን ፡ እንዲሰልሉና ፡ እንዲመረምሩ ፡—
ሂዱ ፡ ምድሪቱንም ፡ ሰልሉ ፡ ብለው ፡ ከጸርዓና ፡
ከኤሽታኦል ፡ ሰደዱ ። እነዚያም ፡ ወደ ፡ ተራራ
ማው ፡ ወደ ፡ ኤፍሬም ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ሚካ ፡
፫ ቤት ፡ መጥተው ፡ በዚያ ፡ አደሩ ። በሚካ ፡ ቤት ፡
አጠገብም ፡ በነበሩ ፡ ጊዜ ፡ የሌዋዊውን ፡ የጐ
ልማሳውን ፡ ድምፅ ፡ አወቁ ፤ ወደ ፡ እርሱም ፡
ቀርበው ፡— ወደዚህ ፡ ማን ፡ አመጣህ ? በዚ
ህስ ፡ የምታደርገው ፡ ምንድር ፡ ነው ? በዚህስ ፡
፬ ምን ፡ አለህ ? አሉት ። እርሱም ፡— ሚካ ፡ እን
ዲህ ፡ እንዲህ ፡ አደረገልኝ ÷ ቀጠረኝም ÷ እኔም ፡
፭ ካህን ፡ ሆንሁለት ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡— የም
ንሄድበት ፡ መንገድ ፡ የቀና ፡ መሆኑን ፡ እና
ውቅ ፡ ዘንድ ÷ እባክህ ÷ እግዚአብሔርን ፡ ጠይ
፮ ቅልን ፡ አሉት ። እርሱም ፡— የምትሄዱበት ፡
መንገድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ነውና ፡ በደ
ኅና ፡ ሂዱ ፡ አላቸው ።
፯ አምስቱም ፡ ሰዎች ፡ ሄዱ ፡ ወደ ፡ ሌሳም ፡
መጡ ÷ በውስጧም ፡ የነበሩትን ፡ ሕዝብ ፡ ተዘ
ልለው ፡ አዩአቸው ÷ እንደ ፡ ሲዶናውያንም ፡
ልማድ ፡ ጸጥ ፡ ብለው ፡ ተዘልለው ፡ ተቀምጠው ፡
ነበር ፤ የሚያስቸግራቸውም ፡ የሚገዛቸውም ፡
አልነበረም ÷ ከሲዶናውያንም ፡ ርቀው ፡ ከሰ
ውም ፡ ሁሉ ፡ ተለይተው ፡ ለብቻቸው ፡ ይኖሩ ፡
፰ ነበር ። ወደ ፡ ወንድሞቻቸውም ፡ ወደ ፡ ጸር
ዓና ፡ ወደ ፡ ኤሽታኦል ፡ ተመለሱ ፤ ወንድሞቻ
ቸውም ፡— ምን ፡ ወሬ ፡ ይዛችኋል ? አሉአ
፱ ቸው ። እነርሱም ፡— ምድሪቱ ፡ እጅግ ፡ መል
ካም ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ አይተናልና ፡ ተነሡ ÷
በእነርሱ ፡ ላይ ፡ እንውጣ ፤ እናንተ ፡ ዝም ፡ ትላ

ላችሁን ? ትሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ምድሪቱንም ፡ ለመ
፲ ውረስ ፡ ትገቡ ፡ ዘንድ ፡ ቸል ፡ አትበሉ ። በሄዳ
ችሁ ፡ ጊዜ ፡ ተዘልለው ፡ ወደ ፡ ተቀመጡ ፡
ሕዝብ ፡ ትደርሳላችሁ ፥ ምድሪቱም ፡ ሰፊ ፡ ናት ፤
እግዚአብሔርም ፡ በምድር ፡ ካለው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡
አንዳች ፡ የማይጐድልበትን ፡ ስፍራ ፡ በእጃችሁ ፡
ሰጥቶአል ፡ አሉ ።

፲፩ ከዳን ፡ ወገንም ፡ የጦር ፡ ዕቃ ፡ የታጠቁ ፡ ስድ
ስት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ከዚያ ፡ ከጾርዓና ፡ ከኤሽ
፲፪ ታኦል ፡ ተነሥተው ፡ ሄዱ ። ወጥተውም ፡ በይ
ሁዳ ፡ ባለችው ፡ በቂርያትይዓሪም ፡ ሰፈሩ ፤ ስለ
ዚህም ፡ የዚያ ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡
የዳን ፡ ሰፈር ፡ ተብሎ ፡ ተጠራ ፤ እነሆም ፥ ከቂ
፲፫ ርያትይዓሪም ፡ በስተ ፡ ኋላ ፡ ነው ። ከዚያም ፡
ወደ ፡ ተራራማው ፡ ወደ ፡ ኤፍሬም ፡ አገር ፡
አለፉ ፤ ወደ ፡ ሚካም ፡ ቤት ፡ መጡ ።

፲፬ የሌሳን ፡ ምድር ፡ ሊሰልሉ ፡ ሄደው ፡ የነበሩት ፡
አምስቱ ፡ ሰዎችም ፡ ወንድሞቻቸውን ፤— በእነ
ዚህ ፡ ቤቶች ፡ ውስጥ ፡ ኤፉድና ፡ ተራፊም ፥
የተቀረጸ ፡ ምስልና ፡ ቀልጠ ፡ የተሠራ ፡ ምስ
ልም ፡ እንዳሉ ፡ ታውቃላችሁን ? አሁንም ፡ የም
ታደርጉትን ፡ ምከሩ ፡ ብለው ፡ ተናገሩአቸው ።
፲፭ ከመንገዱም ፡ ፈቀቅ ፡ ብለው ፡ ጕልማሳው ፡
ሌዋዊ ፡ ወደ ፡ ነበረበት ፡ ወደ ፡ ሚካ ፡ ቤት ፡
፲፮ መጡ ፥ ደኅንነቱንም ፡ ጠየቁት ። የጦር ፡ ዕቃ ፡
የታጠቁት ፥ ከዳን ፡ ልጆችም ፡ የሆኑት ፡ ስድ
ስቱ ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ በደጃፉ ፡ አጠገብ ፡ ቆመው ፡
፲፯ ነበር ። ምድሪቱንም ፡ ሊሰልሉ ፡ ሄደው ፡ የነበ
ሩት ፡ አምስቱ ፡ ሰዎች ፡ ወጥተው ፡ ወደዚያ ፡
ገቡ ፤ የተቀረጸውን ፡ ምስል ፡ ኤፉዱንም ፡ ተራ
ፊሙንም ፡ ቀልጦ ፡ የተሠራውን ፡ ምስልም ፡
ወሰዱ ፤ ካህኑም ፡ የጦር ፡ ዕቃ ፡ ከታጠቁት ፡ ከስ
ድስት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ በደጃፉ ፡ አጠገብ ፡
፲፰ ቆሞ ፡ ነበር ። እነዚህም ፡ ወደ ፡ ሚካ ፡ ቤት ፡
ገብተው ፡ የተቀረጸውን ፡ ምስል ፡ ኤፉዱንም ፡
ተራፊሙንም ፡ ቀልጦ ፡ የተሠራውን ፡ ምስ
ልም ፡ በወሰዱ ፡ ጊዜ ፥ ካህኑ ፤— ምን ፡ ታደርጋ
፲፱ ላችሁ ? አላቸው ። እነርሱም ፤— ዝም ፡ በል ፥
እጅህንም ፡ በአፍህ ፡ ላይ ፡ ጫን ፥ ከእኛም ፡
ጋር ፡ መጥተህ ፡ አባትና ፡ ካህን ፡ ሁንልን ፤ ለአ
ንድ ፡ ሰው ፡ ቤት ፡ ካህን ፡ መሆን ፡ ወይስ ፡ በእ
ስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ለነገድና ፡ ለወገን ፡ ካህን ፡
፳ መሆን ፡ ማናቸው ፡ ይሻልሃል ? አሉት ። ካህ
ኑም ፡ በልቡ ፡ ደስ ፡ አለው ፥ ኤፉዱንም ፡ ተራ
ፊሙንም ፡ የተቀረጸውንም ፡ ምስል ፡ ወሰደ ፥
በሕዝቡም ፡ መካከል ፡ ሄደ ።

፳፩ እነርሱም ፡ ዞረው ፡ ሄዱ ፥ ሕፃናቶችንና ፡ ከብ
ቶችን ፡ ዕቃዎችንም ፡ በፊታቸው ፡ አደረጉ ።
፳፪ ከሚካም ፡ ቤት ፡ በራቁ ፡ ጊዜ ፡ የሚካ ፡ ጐረቤ
ቶች ፡ ተሰበሰቡ ፥ የዳንንም ፡ ልጆች ፡ ተከት
፳፫ ለው ፡ ደረሱባቸው ። ወደ ፡ ዳንም ፡ ልጆች ፡
ጮኹ ፥ የዳንም ፡ ልጆች ፡ ፊታቸውን ፡ መል
ሰው ፡ ሚካን ፤— የምትጮኸው ፡ ምን ፡ ሆነህ ፡
፳፬ ነው ? አሉት ። እርሱም ፤— የሠራኋቸውን ፡
አማልክቴን ፡ ካህኑንም ፡ ይዛችሁ ፡ ሄዳችኋል ፤
ሌላ ፡ ምን ፡ አለኝ ? እናንተስ ፤— ምን ፡ ሆነ
ሃል ፡ እንዴት ፡ ትሉኛላችሁ ? አለ ። ፳፭ የዳንም ፡
ልጆች ፤— የተቈጡ ፡ ሰዎች ፡ እንዳይወድቁብህ ፡
ነፍስህም ፡ የቤተ ፡ ሰቦችህም ፡ ነፍስ ፡ እንዳይ
ጠፋብህ ፥ ድምፅህን ፡ በእኛ ፡ መካከል ፡ አታ
ሰማ ፡ አሉት ። ፳፮ የዳንም ፡ ልጆች ፡ መንገዳቸውን ፡
ሄዱ ፤ ሚካም ፡ ከእርሱ ፡ እንደ ፡ በረቱ ፡ በየ ፡
ጊዜ ፡ ተመልሶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ።

፳፯ እነርሱም ፡ ሚካ ፡ የሠራውን ፡ ጣዖትና ፡ ለእ
ርሱ ፡ የነበረውን ፡ ካህን ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ሌሳ ፥
ጸጥ ፡ ብሎ ፡ ተዘልሎም ፡ ወደ ፡ ተቀመጠው ፡
ሕዝብ ፥ መጡ ፤ በሰይፍም ፡ ስለት ፡ መቱአ
ቸው ፥ ከተማይቱንም ፡ በእሳት ፡ አቃጠሉ
አት ። ፳፰ ከተማይቱ ፡ ከሲዶና ፡ ሩቅ ፡ ያለች ፡
ነበረችና ፥ እነርሱም ፡ ከሌሎች ፡ ሰዎች ፡ ተለ
ይተው ፡ ብቻቸውን ፡ ይኖሩ ፡ ነበርና ፡ የሚ
ታደግ ፡ አልነበራቸውም ። ሌሳም ፡ በቤትሮ
ዖብ ፡ አጠገብ ፡ ባለች ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ ነበረች ።
ከተማይቱንም ፡ ሠርተው ፡ ተቀመጡበት ።
፳፱ ከተማይቱንም ፡ ከእስራኤል ፡ በተወለደው ፡
በአባታቸው ፡ በዳን ፡ ስም ፡ ዳን ፡ ብለው ፡ ጠሩ
አት ፤ የከተማይቱም ፡ ስም ፡ አስቀድሞ ፡ ሌሳ ፡
ነበረ ። ፴ የዳንም ፡ ልጆች ፡ የተቀረጸውን ፡ ምስል ፡
ለራሳቸው ፡ አቆሙ ፤ የሙሴም ፡ ልጅ ፡ የጌር
ሳም ፡ ልጅ ፡ ዮናታን ፥ እርሱና ፡ ልጆቹ ፡ የአ
ገሩ ፡ ሰዎች ፡ እስከሚማረኩበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡
የዳን ፡ ነገድ ፡ ካህናት ፡ ነበሩ ። ፴፩ ሚካም ፡ ያደ
ረገውን ፡ የተቀረጸ ፡ ምስል ፡ የእግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ በሴሎ ፡ ባለበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ አቆሙ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ በዚያም ፡ ዘመን ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡
ንጉሥ ፡ በሌለበት ፡ ጊዜ ፡ በተራራማው ፡ በኤ
ፍሬም ፡ አገር ፡ ማዶ ፡ የተቀመጠ ፡ ሌዋዊ ፡ ነበረ ፤
ከቤተ ፡ ልሔምም ፡ ይሁዳ ፡ ቁባት ፡ አገባ ።
፪ ቁባቱም ፡ አመነዘረችበት ፥ ትታውም ፡ ወደ ፡
አባትዋ ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፡ ይሁዳ ፡
ሄደች ፤ በዚያም ፡ አራት ፡ ወር ፡ ተቀመጠች ።
፫ ባልዋም ፡ ተነሣ ፥ ከእርስዋም ፡ ዕርቅ ፡ ሽቶ ፡
ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሊመልሳት ፡ ፍለጋዋን ፡ ተከተሎ ፡
ሄደ ፤ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ አሽከር ፡ ሁለ
ትም ፡ አህዮች ፡ ነበሩ ። እርስዋም ፡ ወደ ፡ አባ
ትዋ ፡ ቤት ፡ አገባችው ፤ አባትዋም ፡ ባየው ፡
ጊዜ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ተገናኘው ። ፬ የብላቴናይ
ቱም ፡ አባት ፡ አማቱ ፡ የግድ ፡ አለ ፥ በቤቱም ፡
ሦስት ፡ ቀን ፡ ተቀመጠ ፤ በሉም ፥ ጠጡም ፥
በዚያም ፡ አደሩ ። ፭ በአራተኛውም ፡ ቀን ፡ ማል
ደው ፡ ተነሡ ፥ እርሱም ፡ ለመሄድ ፡ ተነሣ ፤
የብላቴናይቱም ፡ አባት ፡ አማቹን ፤— ሰውነት
ህን ፡ በቍራሽ ፡ እንጀራ ፡ አበርታ ፥ ከዚያም ፡
በኋላ ፡ ትሄዳለህ ፡ አለው ። ፮ ተቀመጡም ፡ በአ
ንድ ፡ ላይም ፡ በሉ ፡ ጠጡም ፤ የብላቴናይቱም ፡
አባት ፡ ሰውዮውን ፤— ዛሬ ፡ ደግሞ ፡ ከዚህ ፡ ሰማ

ደር ÷ እባክህ ÷ ፍቀድ ÷ ልብህንም ፡ ደስ ፡ ይበ
፯ ለው ፡ አለው ። ሰውዮውም ፡ ሊሄድ ፡ ተነሣ ፤
አማቱ ፡ ግን ፡ የግድ ፡ አለው ÷ ዳግመኛም ፡
፰ በዚያ ፡ አደረ ። በአምስተኛውም ፡ ቀን ፡ ለመ
ሄድ ፡ ማልዶ ፡ ተነሣ ፤ የብላቴናይቱም ፡ አባት ፡—
እባክህ ÷ ሰውነትህን ፡ አበርታ ÷ ቀኑም ፡ እስኪ
ዋገድ ፡ ድረስ ፡ ቆይ ፡ አለው ። ሁለቱም ፡ በሉ ።
፱ ሰውዮውም ፡ ከቁባቱና ፡ ከአሽከሩ ፡ ጋር ፡ ለመ
ሄድ ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ የብላቴናይቱ ፡ አባት ፡
አማቱ ፡—እነሆ ÷ ቀኑ ፡ ተዋግዶአል ፤ በዚህ ፡
እደሩ ፤ እነሆ ÷ ቀኑ ፡ ለማለፍ ፡ ተዋግዶአል ፤
ልባችሁ ፡ ደስ ፡ እንዲለው ፡ በዚህ ፡ እደሩ ፤
ነገም ፡ ወደ ፡ ቤታችሁ ፡ እንድትደርሱ ፡ ማል
ዳችሁ ፡ መንገዳችሁን ፡ ትሄዳላችሁ ፡ አለው ።
፲ ሰውዮው ፡ ግን ፡ በዚያ ፡ ሌሊት ፡ ለማደር ፡
አልፈቀደም ÷ ተነሥቶም ፡ ሄደ ÷ ኢየሩሳሌ
ምም ፡ ወደ ፡ ተባለች ፡ ወደ ፡ ኢያቡስ ፡ ፊት ፡
ለፊት ፡ ደረሰ ። ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ሁለት ፡ የተ
ጫኑ ፡ አህዮች ፡ ነበሩ ÷ ቁባቱም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
፲፩ ነበረች ። ወደ ፡ ኢያቡስም ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡
መሽቶባቸው ÷ አሽከሩም ፡ ጌታውን ፡— ና ÷ ወደ
ዚህ ፡ ወደ ፡ ኢያቡሳውያን ፡ ከተማ ÷ እባክህ ÷
፲፪ እናቅና ÷ በእርስዋም ፡ እንደር ፡ አለው ። ጌታ
ውም ፡— ከእስራኤል ፡ ወገን ፡ ወዳልሆነች ፡
ወደ ፡ እንግዳ ፡ ከተማ ፡ አንገባም ፤ እኛ ፡ ወደ ፡
፲፫ ጊብዓ ፡ እንለፍ ፡ አለው ። አሽከሩንም ፡— ና ÷
ከእነዚህ ፡ ስፍራ ፡ ወደ ፡ አንዱ ፡ እንቅረብ ፤
በጊብዓ ፡ ወይም ፡ በራማ ፡ እንደር ፡ አለው ።
፲፬ መንገዳቸውንም ፡ ይዘው ፡ ሄዱ ፤ የብንያምም ፡
ነገድ ፡ በምትሆነው ፡ በጊብዓ ፡ አጠገብ ፡ ሳሉ ፡
፲፭ ፀሐይ ፡ ገባችባቸው ። በጊብዓም ፡ ገብተው ፡
ያድሩ ፡ ዘንድ ፡ ወደዚያ ፡ አቀኑ ። በገባም ፡
ጊዜ ፡ ሊያሳድራቸው ፡ ማንም ፡ በቤቱ ፡ አልተ
ቀበላቸውምና ፡ በከተማው ፡ አደባባይ ፡ ተቀ
መጡ ።

፲፮ እነሆም ÷ አንድ ፡ ሽማግሌ ፡ ከእርሻው ፡ ሥራ ፡
ወደ ፡ ማታ ፡ መጣ ፤ ይህም ፡ ሰው ፡ ከተራራ
ማው ፡ ከኤፍሬም ፡ አገር ፡ ነበረ ፡ በጊብዓም ፡
በእንግድነት ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ፤ የዚያ ፡ አገር ፡
፲፯ ሰዎች ፡ ግን ፡ ብንያማውያን ፡ ነበሩ ። ዓይኑ
ንም ፡ አንሥቶ ፡ መንገደኛውን ፡ በከተማው ፡
አደባባይ ፡ አየ ፤ ሽማግሌውም ፡— ወዴት ፡ ትሄዳ
፲፰ ለህ ? ከወዴትስ ፡ መጣህ ? አለው ። እርሱም ፡—
እኛ ፡ ከቤተ ፡ ልሔም ፡ ይሁዳ ፡ ወደ ፡ ተራራ
ማው ፡ ወደ ፡ ኤፍሬም ፡ አገር ፡ ማዶ ፡ እናልፋለን ፤
እኔ ፡ ከዚያ ፡ ነኝ ÷ ወደ ፡ ቤተ ፡ ልሔምም ፡ ይሁዳ ፡
ሄጄ ፡ ነበር ÷ አሁንም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ እሄዳለሁ ፤ በቤቱም ፡ የሚያሳድረኝ ፡
፲፱ አጣሁ ፤ ለአህዮቻችን ፡ ገለባና ፡ ገፈራ ፡ አለን ፤
ለእኔና ፡ ለገረድህ ፡ ከባሪያዎችህም ፡ ጋር ፡
ላለው ፡ አሽከር ፡ እንጀራና ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡
፳ አለን ፤ አንዳችም ፡ አላጣንም ፡ አለው ። ሽማ
ግሌውም ፡— ሰላም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፤
የምትሸውንም ፡ ሁሉ ፡ እኔ ፡ እሰጥሃለሁ ፤ በአ
ደባባይ ፡ ግን ፡ አትደር ፡ አለው ። ወደ ፡ ቤቱም ፡ ፳፩
አስገባው ÷ ለአህዮቹም ፡ ገፈራ ፡ ጣለላቸው ፤
እግራቸውንም ፡ ታጠቡ ÷ በሉም ፡ ጠጡም ።
፳፪ ሰውነታቸውንም ፡ ደስ ፡ ባሰኙ ፡ ጊዜ ፡ ወስ
ላቶች ፡ የሆኑ ፡ የከተማው ፡ ሰዎች ፡ ቤቱን ፡
ከበቡ ፡ በሩንም ፡ ይደበድቡ ፡ ነበር ፤ ባለቤቱንም ፡
ሽማግሌውን ፡— ወደ ፡ ቤትህ ፡ የገባውን ፡ ሰው ፡
፳፫ እንድንደርስበት ፡ አውጣልን ፡ አሉት ። ባለ
ቤቱም ፡ ሽማግሌው ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ወጥቶ ፡—
ወንድሞቼ ፡ ሆይ ÷ ይህን ፡ ክፉ ፡ ነገር ÷ እባክ
ችሁ ÷ አታድርጉ ፤ ይህ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡
ገብቶአልና ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ኃጢአት ፡ አት
፳፬ ሥሩ ። ድንግል ፡ ልጄና ፡ የእርሱም ፡ ቁባት ÷
እነሆ ÷ እሉ ÷ አሁንም ፡ አወጣቸዋለሁ ፤ አዋ
ርዱአቸው ፡ እንደ ፡ ወደዳችሁም ፡ አድርጉብ
ቸው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በዚህ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ እንደ
ዚህ ፡ ያለ ፡ ኃጢአት ፡ አታድርጉ ፡ አላቸው ።
፳፭ ሰዎቹ ፡ ግን ፡ ነገሩን ፡ አልሰሙም ፤ ሰውዮ
ውም ፡ ቁባቱን ፡ ይዞ ፡ አወጣላቸው ፤ ደረሱብ
ትም ÷ ሌሊቱንም ፡ ሁሉ ፡ እስኪነጋ ፡ ድረስ ፡
አመነዘሩባት ፤ ጎህ ፡ በቀደደም ፡ ጊዜ ፡ ለቀቁ
፳፮ አት ። ሴቲቱም ፡ ማለዳ ፡ መጣች ÷ ጌታዋም ፡
በለበት ፡ በሰውዮው ፡ ቤት ፡ ደጅ ፡ ወድቃ ፡ እስ
ኪነጋ ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ ቀረች ።
፳፯ ጌታዋም ፡ ማለዳ ፡ ተነሣ ፡ የቤቱንም ፡ ደጅ ፡
ከፈተ ÷ መንገዱንም ፡ ለመሄድ ፡ ወጣ ፤ እነሆም ፡
ቁባቲቱ ፡ ሴት ፡ በቤቱ ፡ ደጃፍ ፡ ወድቃ ÷ እጅዋም ፡
፳፰ በመድረክ ፡ ላይ ፡ ነበረ ። እርሱም ፡— ተነሺ ÷
እንሂድ ፡ አላት ፤ እርስዋ ፡ ግን ፡ ሞታ ፡ ነበርና ፡
አልመለሰችም ፤ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በአህያው ፡ ላይ ፡
ጫናት ÷ ተነሥቶም ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ሄደ ።
፳፱ ወደ ፡ ቤቱም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ካራ ፡ አንሣ ÷ ቁባ
ቱንም ፡ ይዞ ፡ ከአጥንቶችዋ ፡ መለያያ ፡ ላይ ፡
ለአሥራ ፡ ሁለት ፡ ቁራርጦ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡
፴ አገር ፡ ሁሉ ፡ ሰደደ ። ያየም ፡ ሁሉ ፡— የእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ከወጡ ፡ ጀምሮ ፡
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ከቶ ፡
አልተደረገም ÷ አልታየምም ፤ አስቡት ÷ በዚ
ህም ፡ ተመካከሩ ÷ ተነጋገሩም ፡ ይባባል ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ወጡ ÷ ማኅ
በሩም ፡ ከዳን ፡ እስከ ፡ ቤርሳቤህ ፡ ድረስ ÷ ከገለ
ዓድም ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ጋር ÷ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ወደ ፡ ምጽጳ ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሆነው ፡
፪ ተሰበሰቡ ። ከእስራኤልም ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ የሆኑ ፡
የሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ አለቆች ፡ ሰይፍ ፡ በሚመዝዙ ፡
በቍጥርም ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ እግረኞች ፡
በሆኑ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡ ጉባኤ ፡ ቆሙ ።
፫ የብንያምም ፡ ልጆች ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ወደ ፡ ምጽጳ ፡ እንደ ፡ ወጡ ፡ ሰሙ ። የእስራ
ኤልም ፡ ልጆች ፡— ይህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡
፬ ምን ፡ እንደ ፡ ተደረገ ፡ ንገሩን ፡ አሉ ። የተገደ
ለችውም ፡ ሴት ፡ ባል ፡ ሌዋዊው ፡ እንዲህ ፡

ብሎ ፡ መለሰላቸው ፡— እኔና ፡ ቁባቴ ፡ በዚያ ፡
ለማደር ፡ ወደ ፡ ብንያም ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ጊብዓ ፡
፭፤ መጣን ። የጊብዓም ፡ ሰዎች ፡ ተነሡብኝ ፥ ቤቱ
ንም ፡ በሌሊት ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ ከበቡት ፤ ሊገድ
ሉኝም ፡ ወደዱ ፥ በቁባቴም ፡ አጥብቀው ፡ አመ
፮፤ ነዘሩባት ፥ እርስዋም ፡ ሞተች ። እኔም ፡ ቁበ
ቴን ፡ ይዤ ፡ ቈራረጥኋት ፥ በእስራኤልም ፡
ዘንድ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ኃጢአትና ፡ ስንፍና ፡
ስለ ፡ ተሠራ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ርስት ፡ አገር ፡
፯፤ ሁሉ ፡ ሰደድሁ ። እነሆ ፥ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ሆይ ፥ ሁላችሁ ፥ ምክራችሁንና ፡ እዝናታች
ሁን ፡ በዚህ ፡ ስጡ ።

፰፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ተነ
ሥተው ፡ አሉ ፡— ከእኛ ፡ ዘንድ ፡ ማንም ፡ ወደ ፡
ድንኳኑ ፡ አይሄድም ፥ ወደ ፡ ቤቱም ፡ አይመለ
፱፤ ስም ። ነገር ፡ ግን ፡ በጊብዓ ፡ ላይ ፡ የምናደር
ገው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ በዕጣ ፡ እንወጣባታ
፲፤ ለን ። ወደ ፡ ብንያም ፡ ጊብዓ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡
እርስዋ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ እንዳደረገችው ፡
እንደ ፡ ስንፍናዋ ፡ እንዲያደርጉ ፥ ለሕዝብ ፡
ስንቅ ፡ የሚይዙ ፡ ከእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡
ከመቶው ፡ አሥር ፡ ሰው ፡ ከሺሁም ፡ መቶ ፡
ሰው ፡ ከአሥሩም ፡ ሺህ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ ሰው ፡
፲፩፤ እንወስዳለን ። የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
እንደ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሆነው ፡ በከተማይቱ ፡
ላይ ፡ ተሰበሰቡ ።

፲፪፡፲፫፤ የእስራኤልም ፡ ነገዶች ፡— በእናንተ ፡ መከ
ከል ፡ የተደረገ ፡ ይህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ምንድር ፡
ነው ? አሁንም ፡ እንድንገድላቸው ፡ ከእስራኤ
ልም ፡ ክፉትን ፡ እንድናርቅ ፡ በጊብዓ ፡ ውስጥ ፡
ያሉትን ፡ ምናምንቴዎቹን ፡ ሰዎች ፡ አውጥታ
ችሁ ፡ ስጡን ፡ ብለው ፡ ወደ ፡ ብንያም ፡ ነገድ ፡
ሁሉ ፡ ሰዎችን ፡ላኩ ። የብንያም ፡ ልጆች ፡ ግን ፡
የወንድሞቻቸውን ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡
፲፬፤ ቃል ፡ ሊሰሙ ፡ አልወደዱም ። የብንያምም ፡
ልጆች ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ ሊዋጉ ፡
፲፭፤ ከየከተማው ፡ ወደ ፡ ጊብዓ ፡ ተሰበሰቡ ። በዚ
ያም ፡ ቀን ፡ ከየከተማው ፡ የመጡ ፡ የብንያም ፡
ልጆች ፡ ተቈጠሩ ፤ ቍጥራቸውም ፡ ከጊብዓ ፡
ሰዎች ፡ ሌላ ፡ ሀያ ፡ ስድስት ፡ ሺህ ፡ ሰይፍ ፡ የሚ
መዝዙ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ ከጊብዓም ፡ሰባት ፡ መቶ ፡
፲፮፤ የተመረጡ ፡ ሰዎች ፡ ተቈጠሩ ። ከእነዚያም ፡
ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ የተመረጡ ፡ ግራኝ ፡
ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ እነዚህም ፡ ሁሉ ፡ ድንጋይ ፡ ይወ
ነጭፉ ፡ ነበር ፤ አንዲት ፡ ጠጕርስ ፡ እንኳ ፡ አይ
ስቱም ።

፲፯፤ ከብንያምም ፡ ልጆች ፡ ሌላ ፡ የእስራኤል ፡
ሰዎች ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ ሰይፍ ፡ የሚመ
ዝዙ ፡ ሰዎች ፡ ተቈጠሩ ፤ እነዚህም ፡ ሁሉ ፡ ሰል
፲፰፤ ፈኞች ፡ ነበሩ ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ተነ
ሥተው ፡ ወደ ፡ ቤቴል ፡ ወጡ ፥ እግዚአብሔ
ርንም ፡— የብንያምን ፡ ልጆች ፡ ለመውጋት ፡
አስቀድሞ ፡ ማን ፡ ይውጣልን ? ብለው ፡ ጠየቁት ፤
እግዚአብሔርም ፡— ይሁዳ ፡ ይቅደም ፡ አለ ።

፲፱፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በማለዳ ፡ ተነሥተው ፡
፳፤ በጊብዓ ፡ ፊት ፡ ሰፈሩ ። የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡
ከብንያም ፡ ጋር ፡ ሊዋጉ ፡ ወጡ ፤ የእስራኤልም ፡
ሰዎች ፡ በጊብዓ ፡ አጠገብ ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ተሰ
፳፩፤ ልፈው ፡ ቆሙ ። የብንያምም ፡ ልጆች ፡ ከጊብዓ ፡
ወጡ ፥ በዚያም ፡ ቀን ፡ ከእስራኤላውያን ፡ ሀያ ፡
፳፪፤ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ገደሉ ። ሕዝቡም ፥ የእ
ስራኤል ፡ ሰዎች ፥ ተበራቱ ፥ በፊተኛውም ፡
ቀን ፡ በተሰለፉበት ፡ ስፍራ ፡ ደግመው ፡ ተሰ
፳፫፤ ለፉ ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ወጥተው ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ አለ
ቀሱ ፤ እግዚአብሔርንም ፡— ከወንድሞቻችን ፡
ከብንያም ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ ለመዋጋት ፡ ዳግ
መኛ ፡ እንቀርባለን ? ብለው ፡ ጠየቁ ። እግዚአ
ብሔርም ፡— በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ውጡ ፡ አለ ።

፳፬፤ በሁለተኛውም ፡ ቀን ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ከብንያም ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ ሊዋጉ ፡ ቀረቡ ።
፳፭፤ በሁለተኛውም ፡ ቀን ፡ ብንያም ፡ ከጊብዓ ፡ በእነ
ርሱ ፡ ላይ ፡ ወጣ ፥ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
ደግሞ ፡ አሥራ ፡ ስምንት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ገደሉ ፤
እነዚህም ፡ ሁሉ ፡ ሰይፍ ፡ የሚመዝዙ ፡ ነበሩ ።
፳፮፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡
ወጥተው ፡ ወደ ፡ ቤቴል ፡ መጡ ፥ አለቀሱም ፥
በዚያም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ተቀመጡ ፥
በዚያም ፡ ቀን ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ ጾሙ ፤
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የሚቃጠልና ፡ የደኅን
ነት ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረቡ ። በዚያም ፡ ዘመን ፡ ፳፯፡፳፰፤
የእግዚአብሔር ፡ የቃል ፡ ኪዳኑ ፡ ታቦት ፡ በዚያ ፡
ነበረና ፥ በዚያም ፡ ዘመን ፡ የአሮን ፡ ልጅ ፡ የአ
ልዓዛር ፡ ልጅ ፡ ፊንሐስ ፡ በፊቱ ፡ ይቆም ፡ ነበ
ርና ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እግዚአብሔርን ፡—
ከወንድሞቻችን ፡ ከብንያም ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡
ለመዋጋት ፡ ዳግመኛ ፡ እንውጣን ፡ ወይስ ፡ እን
ቅር ? ብለው ፡ ጠየቁ ። እግዚአብሔርም ፡— ነገ ፡
በእጃችሁ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣቸዋለሁና ፡ ውጡ ፡
አለ ።

፳፱፤ እስራኤልም ፡ በጊብዓ ፡ ዙሪያ ፡ የተደበቁ ፡
፴፤ ሰዎች ፡ አኖሩባት ። በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ የእ
ስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ብንያም ፡ ልጆች ፡
ወጡ ፥ በጊብዓም ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ቀድሞው ፡
፴፩፤ ጊዜ ፡ ተሰለፉ ። የብንያምም ፡ ልጆች ፡ በሕዝቡ ፡
ላይ ፡ ወጡ ፥ ከከተማይቱም ፡ ተሳቡ ፤ እንደ ፡
ቀድሞውም ፡ ጊዜ ፥ በአውራዎቹ ፡ መንገዶች ፥
አንደኛው ፡ ወደ ፡ ቤቴል ፡ ሁለተኛውም ፡
ወደ ፡ ጊብዓ ፡ ሜዳ ፡ በሚወስዱት ፡ መንገዶች ፡
ላይ ፥ ሕዝቡን ፡ ይመቱ ፡ ይገድሉም ፡ ጀመር ፤
ከእስራኤልም ፡ ሠላሳ ፡ የሚያህሉ ፡ ሰዎችን ፡
፴፪፤ ገደሉ ። የብንያምም ፡ ልጆች ፡— እንደ ፡ ቀድ
ሞው ፡ በፊታችን ፡ ተመቱ ፡ አሉ ። የእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ ግን ፡— እንሽሽ ፥ ከከተማም ፡
፴፫፤ ወደ ፡ መንገድ ፡ እንሳባቸው ፡ አሉ ። የእስራኤ
ልም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ከስፍራቸው ፡ ተነሥተው ፡
በበአልታማር ፡ ተሰለፉ ። ከእስራኤልም ፡ ተደ
ብቀው ፡ የነበሩት ፡ ከስፍራቸው ፡ ከጊብዓ ፡ ሜዳ ፡

፴፬ ወጡ ። ከእስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ የተመረጡ ፡
አሥር ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ጊብዓ ፡ አንጻር ፡
መጡ ፤ ሰልፍም ፡ በርትቶ ፡ ነበር ፤ መከራም ፡
፴፭ እንዲያገኛቸው ፡ አላወቁም ፡ ነበር ። እግዚአ
ብሔርም ፡ ብንያምን ፡ በእስራኤል ፡ ፊት ፡ መታ ፤
በዚያም ፡ ቀን ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከብንያም ፡
ሀያ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ አንድ ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡
ገደሉ ፤ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ሰይፍ ፡ የሚመዝዙ ፡
ነበሩ ።

፴፮ የብንያም ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ተመቱ ፡ አዩ ፤
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ በጊብዓ ፡ ላይ ፡ በኖ
ሩት ፡ ድብቅ ፡ ጦር ፡ ታምነዋልና ፡ ለብንያም ፡
፴፯ ስፍራ ፡ ለቀቁላቸው ። ተደብቀውም ፡ የነበሩት ፡
ፈጥነው ፡ ወደ ፡ ጊብዓ ፡ ሮጡ ፤ ተደብቀውም ፡
የነበሩት ፡ መጥተው ፡ ከተማውን ፡ ሁሉ ፡ በሰ
፴፰ ይፍ ፡ ስለት ፡ መቱ ። የተደበቁትም ፡ ሰዎች ፡ ከከ
ተማው ፡ ብዙ ፡ ጢስ ፡ እንደ ፡ ደመና ፡ እንዲያ
ስነሡ ፡ በእስራኤል ፡ ልጆችና ፡ በተደበቁት ፡
ሰዎች ፡ መካከል ፡ ምልክት ፡ ተደርጎ ፡ ነበር ።
፴፱ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ከሰልፉ ፡ አፈገፈጉ ፤
ብንያማውያንም ፡— እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ሰልፍ ፡
በፊታችን ፡ ተመትተዋል ፡ እያሉ ፡ ከእስራኤል ፡
ሰዎች ፡ ሠላሳ ፡ የሚያህሉ ፡ ሰዎች ፡ መምታትና ፡
፵ መግደል ፡ ጀመሩ ። ምልክቱ ፡ በጢሱ ፡ ዓምድ ፡
ከከተማው ፡ ሊወጣ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ ብንያማ
ውያን ፡ ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ተመለከቱ ÷ እነሆም ÷
የሞላ ፡ ከተማው ፡ ጥፋት ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ወጣ ።
፵፩ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ተመለሱ ÷ የብንያምም ፡
ሰዎች ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ደረሰባቸው ፡ አይ
፵፪ ተዋልና ፡ ደነገጡ ። ከእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡
ፊት ፡ ጀርባቸውን ፡ መልሰው ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡
በዳ ፡ መንገድ ፡ ሸሹ ፤ ሰልፉም ፡ ተከታትሎ ፡ ደረ
ሰባቸው ፤ ከየከተማውም ፡ የወጡት ፡ በመካ
፵፫ ከላቸው ፡ ገደሉአቸው ። ብንያማውያንንም ፡
ከበቡ ÷ በምሥራቅም ፡ በኩል ፡ እስካለው ፡
እስከ ፡ ጊብዓ ፡ አንጻር ፡ ድረስ ፡ አሳደዱአቸው ÷
፵፬ በመኑሔም ፡ አጠፉአቸው ። ከብንያምም ፡
አሥራ ፡ ስምንት ፡ ሺህ ፡ ሰው ፡ ሞተ ፤ እነዚህ ፡
፵፭ ሁሉ ፡ ጽኑዓን ፡ ነበሩ ። ከእነርሱም ፡ የተረፉት ፡
ተመልሰው ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወደ ፡ ሬሞን ፡
ዓለት ፡ ሸሹ ÷ ከእነርሱም ፡ በየመንገዱ ፡ ላይ ፡
አምስት ፡ ሺህ ፡ ሰው ፡ ለቀሙ ፤ ወደ ፡ ጊድአ
ምም ፡ አሳደዱአቸው ÷ ከእነርሱም ፡ ሁለት ፡
፵፮ ሺህ ፡ ሰዎችን ፡ ገደሉ ። እንዲሁም ፡ በዚያ ፡
ቀን ፡ ከብንያም ፡ የሞቱት ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡
ሰይፍ ፡ የሚመዝዙ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ እነዚህ ፡
፵፯ ሁሉ ፡ ጽኑዓን ፡ ነበሩ ። ስድስቱም ፡ መቶ ፡
ሰዎች ፡ ተመልሰው ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወደ ፡
ሬሞን ፡ ዓለት ፡ ሸሹ ÷ በሬሞን ፡ ዓለት ፡ አራት ፡
፵፰ ወር ፡ ተቀመጡ ። የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ በብ
ንያም ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ዳግመኛ ፡ ተመለሱ ፤ ሞላ
ውን ፡ ከተማ ፡ ከብቱንም ፡ ያገኙትንም ፡ ሁሉ ፡
በሰይፍ ፡ ስለት ፡ መቱ ፤ ያገኙትንም ፡ ከተማ ፡
ሁሉ ፡ በእሳት ፡ አቃጠሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡— ከእኛ ፡ ማንም ፡
ሰው ፡ ልጁን ፡ ለብንያም ፡ ልጆች ፡ አያጋብ ፡
፪ ብለው ፡ በምጽጳ ፡ ተማምለው ፡ ነበር ። ሕዝቡም ፡
ወደ ፡ ቤቴል ፡ መጥተው ፡ በዚያ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ፊት ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ ተቀመጡ ÷
ድምፃቸውንም ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡ ጽኑ ፡ ልቅሶ ፡
፫ አለቀሱ ። እነርሱም ፡— አቤቱ ÷ የእስራኤል ፡
አምላክ ፡ ሆይ ÷ ዛሬ ፡ ከእስራኤል ፡ አንድ ፡ ነገድ ፡
መታጣቱ ÷ ስለ ፡ ምን ፡ ይህ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡
፬ ሆነ ? አሉ ። በነጋውም ፡ ሕዝቡ ፡ ማልደው ፡
ተነሡ ÷ በዚያም ፡ መሠዊያ ፡ ሠሩ ÷ የሚቃጠ
ልና ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋዕትንም ፡ አቀረቡ ።
፭ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ወደ ፡ ምጽጳ ፡ ስላልወጣ ፡ ሰው ፡— እርሱ ፡ ፈጽሞ ፡
ይገደል ፡ ብለው ፡ ታላቅ ፡ መሐላ ፡ ምለው ፡ ነበ
ርና ፡— ከእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ጉባኤ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያልወጣ ፡ ማን ፡ ነው ?
፮ አሉ ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ስለ ፡ ወንድሞ
ቻቸው ፡ ስለ ፡ ብንያም ፡ ልጆች ፡ ተጸጽተው ፡—
ዛሬ ፡ ከእስራኤል ፡ አንድ ፡ ነገድ ፡ ጠፍቶአል ።
፯ እኛ ፡ ልጆቻችንን ፡ እንዳንድርላቸው ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ ምለናልና ፡ የተረፉት ፡ ሚስቶችን ፡
እንዲያገኙ ፡ ምን ፡ እናድርግ ? አሉ ።
፰ እነርሱም ፡— ከእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ወደ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ምጽጳ ፡ ያልወጣ ፡ ማን ፡ ነው ?
አሉ ። እነሆም ÷ ከኢያቢስ ፡ ገለዓድ ፡ ወደ ፡
ሰፈሩ ፡ ወደ ፡ ጉባኤ ፡ ማንም ፡ አልወጣም ፡ ነበር ።
፱ ሕዝቡም ፡ በተቈጠሩ ፡ ጊዜ ÷ እነሆ ÷ በኢያቢስ ፡
፲ ገለዓድ ፡ የሚኖር ፡ ሰው ፡ አልተገኘም ። ማኅበ
ሩም ፡ ወደዚያ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ኃያላን ፡
ሰዎች ፡ ሰድደው ፡— ሂዱ ፡ በኢያቢስ ፡ ገለዓ
ድም ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ ከሴቶችና ፡ ከሕፃናት ፡
፲፩ ጋር ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ ግደሉ ። የምታደርጉ
ትም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ወንዱን ፡ ሁሉ ÷ ከወንድ ፡
ጋር ፡ የተኛችይቱንም ፡ ሴት ፡ ሁሉ ፡ ፈጽማ
፲፪ ችሁ ፡ አጥፉ ፡ ብለው ፡ አዘዙአቸው ። ወንድ ፡
ያላወቁ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ቈነጃጅት ፡ ደናግሎች ፡
በኢያቢስ ፡ ገለዓድ ፡ በሚኖሩ ፡ መካከል ፡ አገኙ ፤
በከነዓንም ፡ አገር ፡ ወዳለችው ፡ ወደ ፡ ሴሎ ፡
ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ አመጡአቸው ።
፲፫ ማኅበሩም ፡ ሁሉ ፡ በሬሞን ፡ ዓለት ፡ ወዳሉት ፡
ወደ ፡ ብንያም ፡ ልጆች ፡ መልክተኞችን ፡ ላኩ ÷
፲፬ በዕርቅ ፡ ቃልም ፡ ተናገሩአቸው ። በዚያም ፡
ጊዜ ፡ የብንያም ፡ ልጆች ፡ ተመለሱ ፤ ከኢያ
ቢስ ፡ ገለዓድም ፡ ሴቶች ፡ ያዳኑአቸውን ፡ ሴቶች ፡
አገቡአቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ የሚበቁ ፡ ሴቶች ፡
፲፭ አላገኙም ። እግዚአብሔርም ፡ በእስራኤል ፡
ነገድ ፡ ውስጥ ፡ ስብራት ፡ ስላደረገ ፡ ሕዝቡ ፡
ስለ ፡ ብንያም ፡ ተጸጸቱ ።
፲፮ የማኅበሩ ፡ ሽማግሌዎች ፡— ከብንያም ፡
ሴቶች ፡ ጠፍተዋልና ፡ የቀሩት ፡ ሰዎች ፡ ሚስት ፡
፲፯ እንዲያገኙ ፡ ምን ፡ እናደርጋለን ? አሉ ። ደግ

ሞም ፡— ከእስራኤል ፡ አንድ ፡ ነገድ ፡ እንዳይደ
መሰስ ፡ ከብንያም ፡ ላመለጡት ፡ ርስት ፡ ይኑር ።
፲፰ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡— ልጁን ፡ ለብንያም ፡
የሚድር ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፡ ብለው ፡ ምለዋልና ፡
እኛ ፡ ልጆቻችንን ፡ ለእነርሱ ፡ ማጋባት ፡ አይሆ
፲፱ ንልንም ፡ አሉ ። እነርሱም ፡— እነሆ ፥ በቤቴል ፡
በሰሜን ፡ በኩል ፥ ከቤቴልም ፡ ወደ ፡ ሴኬም ፡
በሚወስደው ፡ መንገድ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፥
በለቦና ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ባለችው ፡ በሴሎ ፡
የእግዚአብሔር ፡ በዓል ፡ በየዓመቱ ፡ አለ ፡ አሉ ።
፳ የብንያምንም ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ አዘ
ዙአቸው ፡— ሂዱ ፡ በወይኑም ፡ ስፍራ ፡ ተደ
፳፩ በቁ ፤ ተመልከቱም ፥ እነሆም ፥ የሴሎ ፡ ሴቶች ፡
ልጆች ፡ አታሞ ፡ ይዘው ፡ ለዘፈን ፡ ሲወጡ ፡
ከወይኑ ፡ ስፍራ ፡ ውጡ ፥ ከሴሎም ፡ ሴቶች ፡
ልጆች ፡ ለየራሳችሁ ፡ ሚስት ፡ ንጠቁ ፥ ወደ ፡
፳፪ ብንያም ፡ ምድርም ፡ ሂዱ ። አባቶቻቸውና ፡
ወንድሞቻቸውም ፡ ሊጣሉአችሁ ፡ ወደ ፡ እኛ ፡
በመጡ ፡ ጊዜ ፡— ስለ ፡ እኛ ፡ ማሩአቸው ፤ እኛ ፡
ሚስት ፡ ለያንዳንዳቸው ፡ በሰልፍ ፡ አልወሰድ
ንላቸውምና ፥ እናንተም ፡ በደል ፡ ይሆንባችሁ ፡
ስለ ፡ ነበረ ፡ አላጋባችኋቸውምና ፥ እንላችኋ
ለን ። ፳፫ የብንያምም ፡ ልጆች ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ፥
በቍጥራቸውም ፡ መጠን ፡ ከተነጠቁት ፡ ዘፋ
ኞች ፡ ሚስት ፡ ወሰዱ ፤ ወደ ፡ ርስታቸውም ፡ ተመ
ልሰው ፡ ሄዱ ፥ ከተሞችንም ፡ ሠርተው ፡ ተቀ
መጡባቸው ። ፳፬ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ የእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ከዚያ ፡ ተነሡ ፥ እያንዳንዱም ፡ ወደ ፡
ነገዱና ፡ ወደ ፡ ወገኑ ፡ ሄደ ፤ ሰውም ፡ ሁሉ ፡
ከዚያ ፡ ወደ ፡ ርስቱ ፡ ተመለሰ ።

፳፭ በዚያም ፡ ዘመን ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ንጉሥ ፡
አልነበረም ፤ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ መልካም ፡
መስሎ ፡ የታየውን ፡ ያደርግ ፡ ነበር ።

# መ ጽ ሐ ፈ ፡ ሩ ት ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ መሳፍንት ፡ ይፈርዱ ፡ በነ
በረ ፡ ጊዜ ፡ በአገሩ ፡ ላይ ፡ ራብ ፡ ሆነ ። አንድ ፡
ሰውም ፡ ከሚስቱና ፡ ከሁለቱ ፡ ልጆቹ ፡ ጋር ፡
በሞዓብ ፡ ምድር ፡ ሊቀመጥ ፡ ከቤተ ፡ ልሔም ፡
፪ ይሁዳ ፡ ተነሥቶ ፡ ሄደ ። የሰውዮውም ፡ ስም ፡
አቤሜሌክ ፥ የሚስቱም ፡ ስም ፡ ኑኃሚን ፥ የሁ
ለቱም ፡ ልጆች ፡ ስም ፡ መሐሎንና ፡ ኬሌዎን ፡
ነበረ ፤ የቤተ ፡ ልሔም ፡ ይሁዳም ፡ የኤፍራታ ፡
ሰዎች ፡ ነበሩ ። ወደ ፡ ሞዓብም ፡ ምድር ፡ መጡ ፡
፫ በዚያም ፡ ተቀመጡ ። የኑኃሚንም ፡ ባል ፡ አቤ
ሜሌክ ፡ ሞተ ፤ እርስዋና ፡ ሁለቱ ፡ ልጆችዋ ፡
፬ ቀሩ ። እነርሱም ፡ ከሞዓባውያን ፡ ሴቶች ፡
ሚስት ፡ አገቡ ፤ የአንዲቱ ፡ ስም ፡ ዖርፋ ፡ የሁ
ለተኛይቱም ፡ ስም ፡ ሩት ፡ ነበረ ። በዚያም ፡
፭ አሥር ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ ተቀመጡ ። መሐሎ
ንና ፡ ኬሌዎንም ፡ ሁለቱ ፡ ሞቱ ፤ ሴቲቱም ፡ ከሁ
ለቱ ፡ ልጆችዋና ፡ ከባልዋ ፡ ተለይታ ፡ ቀረች ።
፮ እርስዋም ፡ በሞዓብ ፡ ምድር ፡ ሳለች ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ እንደ ፡ ጐበኘ ፡ እንጀራም ፡
እንደ ፡ ሰጣቸው ፡ ስለ ፡ ሰማች ፥ ከሞዓብ ፡
ምድር ፡ ልትመለስ ፡ ከሁለቱ ፡ ምራቶችዋ ፡ ጋር ፡
፯ ተነሣች ። እርስዋም ፡ ከሁለቱ ፡ ምራቶችዋ ፡
ጋር ፡ ከተቀመጠችበት ፡ ስፍራ ፡ ወጣች ፤ ወደ ፡
ይሁዳም ፡ ምድር ፡ ሊመለሱ ፡ በመንገድ ፡ ሄዱ ።
፰ ኑኃሚንም ፡ ምራቶችዋን ፡— ሂዱ ፥ ወደ ፡
እናቶቻችሁም ፡ ቤት ፡ ተመለሱ ፤ በእኔና ፡ በሞ
ቱት ፡ እንዳደረጋችሁ ፥ እግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡
፱ ያድርግላችሁ ። እግዚአብሔር ፡ በየባላችሁ ፡
ቤት ፡ ዕረፍት ፡ ይስጣችሁ ፡ አለቻቸው ። ሳመ
ቻቸውም ፤ ድምፃቸውንም ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡
፲ አለቀሱ ። እነርሱም ፡— ከአንቺ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡
ሕዝብሽ ፡ እንመለሳለን ፡ አሉአት ። ፲፩ ኑኃሚንም ፡
አለች ፡— ልጆቼ ፡ ሆይ ፥ ተመለሱ ፤ ለምን ፡
ከእኔ ፡ ጋር ፡ ትሄዳላችሁ ? ባሎቻችሁ ፡ የሚ
ሆኑ ፡ ልጆች ፡ በሆዴ ፡ አሉኝን ? ፲፪ ልጆቼ ፡ ሆይ ፥
ተመለሱ ፤ ባል ፡ ለማግባት ፡ አርጅቻለሁና ፡ ሂዱ ፤
ተስፋ ፡ አለኝ ፡ ብል ፥ ዛሬ ፡ ሌሊትስ ፡ እንኳ ፡
ባል ፡ ባገባ ፥ ወንዶች ፡ ልጆችም ፡ ብወልድ ፥
፲፫ እነርሱ ፡ እስኪያድጉ ፡ ድረስ ፡ ትቆያላችሁን ?
ስለ ፡ እነርሱስ ፡ ባል ፡ ማግባት ፡ ትተዋላችሁን ?
ልጆቼ ፡ ሆይ ፥ እንዲህ ፡ አይደለም ፤ የእግዚአ
ብሔር ፡ እጅ ፡ በእኔ ፡ ወጥቶአልና ፡ ከእናንተ ፡
የተነሣ ፡ እጅግ ፡ ተመርሬአለሁ ። ፲፬ ድምፃቸው
ንም ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡ እንደ ፡ ገና ፡ አለቀሱ ፤
ዖርፋም ፡ አማትዋን ፡ ሳመች ፤ ሩት ፡ ግን ፡ ተጠ
ጋቻት ። ፲፭ ኑኃሚንም ፡— እነሆ ፥ ባልንጀራሽ ፡
ወደ ፡ ሕዝብዋና ፡ ወደ ፡ አማልክትዋ ፡ ተመልሳ
ለች ፤ አንቺም ፡ ደግሞ ፡ ከባልንጀራሽ ፡ ጋር ፡ ተመ
ለሽ ፡ አለቻት ። ፲፮ ሩትም ፡— ወደምትሄጅበት ፡
እሄዳለሁና ፥ በምታድሪበትም ፡ አድራለሁና ፡
እንድተውሽ ፡ ከአንቺም ፡ ዘንድ ፡ እንድመለስ ፡
አታስቸግሪኝ ፤ ሕዝብሽ ፡ ሕዝቤ ፥ አምላክሽም ፡
አምላኬ ፡ ይሆናል ፤ ፲፯ በምትሞችበትም ፡ ስፍራ ፡
እሞታለሁ ፥ በዚያም ፡ እቀበራለሁ ፤ ከሞት ፡
በቀር ፡ አንቺንና ፡ እኔን ፡ አንዳች ፡ ቢለየን ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ያድርግብኝ ፡ እንዲሁም ፡
ይጨምርብኝ ፡ አለች ። ፲፰ ኑኃሚንም ፡ ከእርስዋ ፡
ጋር ፡ ለመሄድ ፡ እንደ ፡ ቈረጠች ፡ በየች ፡ ጊዜ ፡
እርስዋን ፡ ከመናገር ፡ ዝም ፡ አለች ።

፲፱ ሁለቱም ፡ እስከ ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፡ ድረስ ፡
ሄዱ ። ወደ ፡ ቤተ ፡ ልሔምም ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡
የከተማይቱ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡—

ይህች ፡ ኑኃሚን ፡ ናትን ? እያሉ ፡ ተንጫጩ ።
፳ እርስዋም ፡— ሁሉን ፡ የሚችል ፡ አምላክ ፡ አስ
መርሮኛልና ፡ ማራ ፡ በሉኝ ፡ እንጂ ፡ ኑኃሚን ፡
፳፩ አትበሉኝ ። በሙላት ፡ ወጣሁ ÷ እግዚአብሔ
ርም ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ በዶዬን ፡ መለሰኝ ፤ እግዚአ
ብሔር ፡ አዋርዶኛልና ÷ ሁሉንም ፡ የሚችል ፡
አምላክ ፡ አስጨንቆኛልና ፡ ኑኃሚን ፡ ለምን ፡
፳፪ ትሉኛላችሁ ? አለቻቸው ። ኑኃሚንም ፡ ከእ
ርስዋም ፡ ጋር ፡ ከሞዓብ ፡ ምድር ፡ የተመለሰ
ችው ፡ ሞዓባዊቱ ፡ ምራትዋ ፡ ሩት ፡ ተመለሱ ።
የገብስም ፡ መከር ፡ በተጀመረ ፡ጊዜ ፡ ወደ ፡
ቤተ ፡ ልሔም ፡ መጡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ለኑኃሚንም ፡ ባል ፡ የሚዘመደው ፡ ከአቤሜ
ሌክ ፡ ወገን ፡ የሆነ ፡ ኃያል ፡ ሰው ፡ ስሙ ፡ ቦዔዝ ፡
፪ የተባለ ፡ ሰው ፡ ነበረ ። ሞዓባዊቱም ፡ ሩት ፡
ኑኃሚንን ፡— በፊቱ ፡ ሞገስ ፡ የማገኘውን ፡ ተከ
ትዬ ፡ እሀል ፡ እንድቃርም ፡ ወደ ፡ እርሻ ፡ ልሂድ ፡
አለቻት ። እርስዋም ፡— ልጄ ፡ ሆይ ÷ ሂጂ ፡
፫ አለቻት ። ሄደችም ÷ ከአጫጆችም ፡ በኋላ ፡
በእርሻ ፡ ውስጥ ፡ ቃረመች ፤ እንደ ፡ አጋጣሚ
ውም ፡ የአቤሜሌክ ፡ ወገን ፡ ወደ ፡ ነበረው ፡
፬ ወደ ፡ ቦዔዝ ፡ እርሻ ፡ ደረሰች ። እነሆም ÷ ቦዔዝ ፡
ከቤተ ፡ ልሔም ፡ መጣ ÷ አጫጆችንም ፡— እግ
ዚአብሔር ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፡ አላቸው ።
እነርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡ ይባርክህ ፡ ብለው ፡
፭ መለሱለት ። ቦዔዝም ፡ በአጫጆች ፡ ላይ ፡
አዛዥ ፡ የነበረውን ፡ ሎሌውን ፡— ይህች ፡
፮ ቆንጆ ፡ የማን ፡ ናት ? አለው ። የአጫጆቹም ፡
አዛዥ ፡— ይህችማ ፡ ከሞዓብ ፡ ምድር ፡ ከኑኃ
ሚን ፡ ጋር ፡ የመጣች ፡ ሞዓባዊቱ ፡ ቆንጆ ፡ ናት ፤
፯ እርስዋም ፡— ከአጫጆቹ ፡ በኋላ ፡ በነዶው ፡
መካከል ፡ እንድቃርምና ፡ እንድለቅም ÷ እባ
ክህ ÷ ፍቀድልኝ ፡ አለች ፤ መጣችም ÷ ከማለ
ዳም ፡ ጀምራ ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ ድረስ ፡ ቆይታ
ለች ፤ በቤትም ፡ ጥቂት ፡ ጊዜ ፡ እንኳ ፡ አላረፈ
ችም ፡ አለው ።
፰ ቦዔዝም ፡ ሩትን ፡— ልጄ ፡ ሆይ ÷ ትሰሚያለ
ሽን ? ቃርሚያ ፡ ለመቃረም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ እርሻ ፡
አትሂጂ ÷ ከዚህም ፡ አትላወሺ ÷ ነገር ፡ ግን ፡
፱ ገረዶቼን ፡ ተጠጊ ። ወደሚያጭዱበትም ፡
ስፍራ ፡ ተመልከቺ ÷ ተከተያቸውም ፤ እንዳያ
ስቸግሩሽም ፡ ጐበዛዝቱን ፡ አዝዣለሁ ፤ በተ
ጠማሽም ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ማድጋው ፡ ሄደሽ ፡ ጐበ
፲ ዛዝቱ ፡ ከቀዱት ፡ ውኃ ፡ ጠጪ ፡ አላት ። በግም
ባርዋም ፡ ተደፍታ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ሰገደች
ለት ፡— እኔንስ ፡ ለመቀበል ፡ በምን ፡ ነገር ፡ በፊ
ትህ ፡ ሞገስ ፡ አገኘሁ ? እኔ ፡ እንግዳ ፡ አይደለ
፲፩ ሁምን ? አለችው ። ቦዔዝም ፡— ባልሽ ፡ ከሞተ ፡
በኋላ ፡ አባትሽንና ፡ እናትሽን ፡ የተወለድሽበ
ትንም ፡ ምድር ፡ ትተሽ ፡ ቀድሞ ፡ ወደማታው
ቂው ፡ ሕዝብ ፡ እንደ ፡ መጣሽ ÷ ለአማትሽ ፡ ያደ
ረግሽውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሞ ፡ ሰምቻለሁ ።
፲፪ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሥራሽ ፡ ይስጥሽ ፤ ከክ
ንፉም ፡ በታች ፡ መጠጊያ ፡ እንድታገኚ ፡ በመ
ጣሽበት ፡ በእስራኤል ፡ አምላክ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ዘንድ ፡ ደመወዝሽ ፡ ፍጹም ፡ ይሁን ፡
፲፫ አላት ። እርስዋም ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ÷ ከባሪያዎ
ችህ ፡ እንደ ፡ አንዲቱ ፡ ሳልሆን ፡ አጽናንተኸኛ
ልና ÷ የባሪያህንም ፡ ልብ ፡ ደስ ፡ አሰኘተሃልና ፡
በዓይንህ ፡ ሞገስ ፡ ላግኝ ፡ አለችው ።
፲፬ በምሳም ፡ ጊዜ ፡ ቦዔዝ ፡— ወደዚህ ፡ ቅረቢ ፤
ምሳ ፡ ብዪ ÷ እንጀራሽንም ፡ በሆምጣጤው ፡ አጥ
ቅሽ ፡ አላት ። በአጫጆቹም ፡ አጠገብ ፡ ተቀመ
ጠች ፡ የተጠበሰም ፡ እሸት ፡ ሰጣት ÷ በልታም ፡
፲፭ ጠገበች ÷ አተረፈችም ። ደግሞም ፡ ልትቃ
ርም ፡ በተነሣች ፡ ጊዜ ፡ ቦዔዝ ፡ ጐበዛዝቱን ፡—
በነዶው ፡ መካከል ፡ ትቃርም ÷ እናንተም ፡ አታ
፲፮ ሳፍሩአት ፤ ደግሞ ፡ ከነዶው ፡ አስቀርታችሁ ፡
ተዉላት ፤ እርስዋም ፡ ትቃርም ÷ አትውቀሱ
አትም ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ።
፲፯ በእርሻውም ፡ ውስጥ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡
ቃረመች ፤ የቃረመችውንም ፡ ወቃችው ፤
አንድ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ ያህልም ፡ ገብስ ፡
፲፰ ሆነ ። ተሸክማውም ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ገባች ÷
አማትዋም ፡ የቃረመችውን ፡ አየች ፤ ከጠገበ
ችም ፡ በኋላ ፡ የተረፋትን ፡ አውጥታ ፡ ሰጠቻት ።
፲፱ አማትዋም ፡— ዛሬ ፡ ወዴት ፡ ቃረምሽ ? ወዴ
ትስ ፡ ሠራሽ ? የተቀበለሽ ፡ የተባረከ ፡ ይሁን ፡
አለቻት ። እርስዋም ፡— ዛሬ ፡ የሠራሁበት ፡
ሰው ፡ ስም ፡ ቦዔዝ ፡ ይባላል ፡ ብላ ፡ በማን ፡
ዘንድ ፡ እንደ ፡ ሠራች ፡ ለአማትዋ ፡ ነገረቻት ።
፳ ኑኃሚንም ፡ ምራትዋን ፡— ቸርነቱን ፡ በሕያዋ
ንና ፡ በሙታን ፡ ላይ ፡ ያልተወ ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ የተባረከ ፡ ይሁን ፡ አለቻት ። ኑኃሚ
ንም ፡ ደግሞ ፡— ይህ ፡ ሰው ፡ የቅርብ ፡ ዘመዳ
ችን ፡ ነው ÷ እርሱም ፡ ሊቤዡን ፡ ከሚችሉት ፡
፳፩ አንዱ ፡ ነው ፡ አለቻት ። ሞዓባዊቱ ፡ ሩትም ፡—
ደግሞ ፡— መከሬን ፡ እስኪጨርሱ ፡ ድረስ ፡ ጐበ
፳፪ ዛዝቴን ፡ ተጠጊ ፡ አለኝ ፡ አለቻት ። ኑኃሚንም ፡
ምራትዋን ፡ ሩትን ፡— ልጄ ፡ ሆይ ÷ ከገረዶቹ ፡
ጋር ፡ ብትወጪ ÷ በሌላም ፡ እርሻ ፡ ባያገኙሽ ፡
፳፫ መልካም ፡ ነው ፡ አለቻት ። ሩትም ፡ የገብሱና ፡
የስንዴው ፡ መከር ፡ እስኪጨረስ ፡ ድረስ ፡ ልት
ቃርም ፡ የቦዔዝን ፡ ገረዶች ፡ ተጠጋች ፤ በአማ
ትዋም ፡ ዘንድ ፡ ትቀመጥ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ አማትዋም ፡ ኑኃሚን ፡ አለቻት ፡— ልጄ ፡
ሆይ ÷ መልካም ፡ እንዲሆንልሽ ፡ ዕረፍት ፡ አል
፪ ፈልግልሽምን ? አሁንም ፡ ከገረዶቹ ፡ ጋር ፡ የነበ
ርሽበት ፡ ቦዔዝ ፡ ዘመዳችን ፡ አይደለምን ?
እነሆ ÷ እርሱ ፡ በዛሬ ፡ ሌሊት ፡ በአውድማው ፡
፫ ላይ ፡ ገብሱን ፡ በመንሽ ፡ ይበትናል ። እንግ
ዲህ ፡ ታጠቢ ÷ ተቀቢ ÷ ልብስሽን ፡ ተላበሺ ÷
ወደ ፡ አውድማውም ፡ ውረጂ ፤ ነገር ፡ ግን ፡
መብሉንና ፡ መጠጡን ፡ እስኪጨርስ ፡ ድረስ ፡

፬ ለሰውዮው ፡ አትታዩው ። በተኛም ፡ ጊዜ ፡
የሚተኛበትን ፡ ስፍራ ፡ ተመልከቺ ፥ ገብተ
ሽም ፡ እግሩን ፡ ግለጪ ፥ ተጋደሚም ፤ የምታ
፭ ደርጊውንም ፡ እርሱ ፡ ይነግርሻል ። ሩትም ፡—
የተናገርሽኝን ፡ ሁሉ ፡ አደርጋለሁ ፡ አለቻት ።
፮ ወደ ፡ አውድማውም ፡ ወረደች ፥ አማት
፯ ዋም ፡ ያዘዘቻትን ፡ ሁሉ ፡ አደረገች ። ቦዔዝም ፡
ከበላና ፡ ከጠጣ ፡ ሰውነቱንም ፡ ደስ ፡ ካሰኘ ፡
በኋላ ፥ በእህሉ ፡ ክምር ፡ አጠገብ ፡ ሊተኛ ፡
ሄደ ፤ ሩትም ፡ በቀስታ ፡ መጣች ፥ እግሩንም ፡
፰ ገልጣ ፡ ተኛች ። መንፈቀ ፡ ሌሊትም ፡ በሆነ ፡
ጊዜ ፡ ሰውዮው ፡ ደነገጠ ፥ ዘወርም ፡ አለ ፤ እነ
ሆም ፥ አንዲት ፡ ሴት ፡ በእግርጌው ፡ ተኝታ ፡
፱ ነበረች ። እርሱም ፡— ማን ፡ ነሽ ? አለ ። እርስ
ዋም ፡— እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ሩት ፡ ነኝ ፤ ዋርሳዬ ፡ ነህና ፡
ልብስህን ፡ በባሪያህ ፡ ላይ ፡ ዘርጋ ፡ አለችው ።
፲ ቦዔዝም ፡ አላት ፡— ልጄ ፡ ሆይ ፥ በእግዚአብ
ሔር ፡ የተባረክሽ ፡ ሁኚ ፤ ባለጠጋም ፡ ድሀም ፡
ብለሽ ፡ ጕበዛዝትን ፡ አልተከተልሽምና ፡ ከፊ
ተኛው ፡ ይልቅ ፡ በመጨረሻው ፡ ጊዜ ፡ ቸርነት ፡
፲፩ አድርገሻል ። አሁንም ፥ ልጄ ፡ ሆይ ፥ አትፍሪ ፤
በአገሬ ፡ ያሉ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ምግባረ ፡ መል
ካም ፡ ሴት ፡ እንደ ፡ ሆንሽ ፡ ያውቃሉና ፡ ያልሽ
፲፪ ውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አደርግልሻለሁ ። የቅርብ ፡
ዘመድ ፡ መሆኔ ፡ እውነት ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡
፲፫ ከእኔ ፡ የቀረበ ፡ ዘመድ ፡ አለ ። ዛሬ ፡ ሌሊት ፡
እደሪ ፤ ነገም ፡ እርሱ ፡ ዋርሳ ፡ መሆን ፡ ቢወድድ ፡
መልካም ፡ ነው ፥ ዋርሳ ፡ ይሁን ፤ ዋርሳ ፡ ሊሆን ፡
ባይወድድ ፡ ግን ፥ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! እኔ ፡
ዋርሳ ፡ እሆንሻለሁ ፤ እስኪነጋ ፡ ድረስ ፡ ተኚ ።
፲፬ እስኪነጋም ፡ በእግርጌው ፡ ተኛች ፤ ቦዔዝም ፡—
ሴት ፡ ወደ ፡ አውድማው ፡ እንደ ፡ መጣች ፡
ማንም ፡ እንዳያውቅ ፡ ብሎ ፡ ነበርና ፡ ገና ፡
፲፭ ሰውና ፡ ሰው ፡ ሳይተያይ ፡ ተነሣች ። እር
ሱም ፡— የለበስሽውን ፡ ኩታ ፡ አምጥተሽ ፡
ያዢው ፡ አላት ፤ በያዘችም ፡ ጊዜ ፡ ስድስት ፡
መስፈሪያ ፡ ገብስ ፡ ሰፈረላት ፡ አሸከማትም ።
፲፮ እርሱም ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ ሄደ ። ወደ ፡ አማ
ትዋም ፡ መጣች ፥ አማትዋም ፡— ልጄ ፡ ሆይ ፥
እንዴት ፡ ነሽ ? አለቻት ፤ እርስዋም ፡ ሰውዮው ፡
፲፯ ያደረገላትን ፡ ሁሉ ፡ ነገረቻት ። ወደ ፡ አማ
ትሽ ፡ ባዶ ፡ እጅሽን ፡ አትሂጂ ፡ ብሎ ፡ ይህን ፡
፲፰ ስድስት ፡ መስፈሪያ ፡ ገብስ ፡ ሰጠኝ ፡ አለቻት ። እር
ስዋም ፡— ልጄ ፡ ሆይ ፥ ሰውዮው ፡ ይህን ፡ ነገር ፡
ዛሬ ፡ እስኪጨርስ ፡ ድረስ ፡ አያርፍምና ፡ ፍጻ
ሜው ፡ እስኪታወቅ ፡ ድረስ ፡ ዝም ፡ በዪ ፡ አለች ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ቦዔዝም ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ በር ፡ አደባባይ ፡
ወጥቶ ፡ በዚያ ፡ ተቀመጠ ። እነሆም ፥ ቦዔዝ ፡
ስለ ፡ እርሱ ፡ ይናገር ፡ የነበረው ፡ የቅርብ ፡ ዘመድ ፡
ሲያልፍ ፡ ቦዔዝ ፡— አንተ ፡ ቀርበህ ፡ በዚህ ፡
ተቀመጥ ፡ አለው ። እርሱም ፡ ቀረብ ፡ ብሎ ፡ ተቀ
፪ መጠ ። ቦዔዝም ፡ ከከተማይቱ ፡ ሽማግሌዎች ፡
አሥር ፡ ሰዎች ፡ ጠርቶ ፡— በዚህ ፡ ተቀመጡ ፡
፫ አላቸው ። እነርሱም ፡ ተቀመጡ ። ቦዔዝም ፡
የቅርብ ፡ ዘመዱን ፡— ከሞዓብ ፡ ምድር ፡ የተመ
ለሰችው ፡ ኑኃሚን ፡ የወንድማችንን ፡ የአቤሜ
፬ ሌክን ፡ ጢንጦ ፡ ትሸጣለች ። እኔም ፡ በዚህ ፡
በተቀመጡት ፡ በሕዝቤ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ፊት ፡
እንድትገዛው ፡ አስታውቅህ ፡ ዘንድ ፡ አሰብሁ ።
መቤዠት ፡ ብትወድድ ፡ ተቤዠው ፤ መቤዠት ፡
ባትወድድ ፡ ግን ፡ ከአንተ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ወራሽ ፡
የለምና ፥ እኔም ፡ ከአንተ ፡ በኋላ ፡ ነኝና ፡ እንዳ
ውቀው ፡ ንገረኝ ፡ አለው ። እርሱም ፡— እቤዠ
፭ ዋለሁ ፡ አለው ። ቦዔዝም ፡— እርሻውን ፡ ከኑ
ኃሚን ፡ እጅ ፡ በምትገዛበት ፡ ቀን ፥ ለሞተው ፡
በርስቱ ፡ ስሙን ፡ እንድታስነሣለት ፡ ከምዋቹ ፡
ሚስት ፡ ከሞዓባዊቱ ፡ ከሩት ፡ ደግሞ ፡ ትገዛለህ ፡
፮ አለ ። የቅርብ ፡ ዘመዱም ፡— የራሴን ፡ ርስት ፡
እንዳላበላሽ ፡ መቤዠት ፡ አልችልም ፤ እኔ ፡
መቤዠቱን ፡ አልችልምና ፡ አንተ ፡ ከእኔ ፡ መቤ
ዠቱን ፡ ውሰደው ፡ አለ ።
፯ በጥንት ፡ ጊዜም ፥ ማንም ፡ ቢሸጥ ፡ ቢለው
ጥም ፥ ነገሩን ፡ ለማጽናት ፡ ሰው ፡ ጫማውን ፡
እንዲያወልቅ ፡ ለባልንጀራውም ፡ እንዲሰጠው ፡
በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ልማድ ፡ ነበረ ። ይህም ፡ በእ
፰ ስራኤል ፡ ምስክር ፡ ነበረ ። የቅርብ ፡ ዘመዱም ፡
ቦዔዝን ፡— አንተ ፡ ግዛው ፡ አለው ፤ ጫማው
፱ ንም ፡ አወለቀ ። ቦዔዝም ፡ ሽማግሌዎችንና ፡
ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡— ለአቤሜሌክና ፡ ለኬሌዎን ፡
ለመሐሎንም ፡ የነበረውን ፡ ሁሉ ፡ ከኑኃሚን ፡
እጅ ፡ እንደ ፡ ገዛሁ ፡ እናንተ ፡ ዛሬ ፡ ምስክሮች ፡
፲ ናችሁ ። ደግሞም ፡ የምዋቹ ፡ ስም ፡ ከወንድ
ሞቹ ፡ መካከል ፡ ከአገሩም ፡ ደጅ ፡ እንዳይጠፋ ፥
የምዋቹን ፡ ስም ፡ በርስቱ ፡ ላይ ፡ እንዳስነሣ ፡
የመሐሎንን ፡ ሚስት ፡ ሞዓባዊቱን ፡ ሩትን ፡
ሚስት ፡ ትሆነኝ ፡ ዘንድ ፡ ወሰድሁአት ፤ እና
ንተም ፡ ዛሬ ፡ ምስክሮች ፡ ናችሁ ፡ አላቸው ።
፲፩ በከተማይቱ ፡ በር ፡ አደባባይም ፡ የነበሩ ፡ ሕዝብ ፡
ሁሉ ፡ ሽማግሌዎቹም ፡— እኛ ፡ ምስክሮች ፡ ነን ፤
እግዚአብሔር ፡ ይህችን ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ የምት
ገባውን ፡ ሴት ፡ የእስራኤልን ፡ ቤት ፡ እንደ ፡
ሠሩ ፡ እንደ ፡ ሁለቱ ፡ እንደ ፡ ራሔልና ፡ እንደ ፡
ልያ ፡ ያድርጋት ፤ አንተም ፡ በኤፍራታ ፡ ባለ
ጠጋ ፡ ሁን ፥ ስምህም ፡ በቤተ ፡ ልሔም ፡ ይጠራ ።
፲፪ ቤትህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከዚህች ፡ ቈንጆ ፡ ከሚ
ሰጥህ ፡ ዘር ፡ ትዕማር ፡ ለይሁዳ ፡ እንደ ፡ ወለደ
ችው ፡ እንደ ፡ ፋሬስ ፡ ቤት ፡ ይሁን ፡ አሉት ።
፲፫ ቦዔዝም ፡ ሩትን ፡ ወሰደ ፥ ሚስትም ፡ ሆነ
ችው ፤ ደረሰባትም ፥ እግዚአብሔርም ፡ ፅንስ ፡
፲፬ ሰጣት ፥ ወንድ ፡ ልጅም ፡ ወለደች ። ሴቶችም ፡
ኑኃሚንን ፡— ዛሬ ፡ ዋርሳ ፡ ያላሳጣሽ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ይባረክ ፤ ስሙም ፡ በእስራኤል ፡ ይጠራ ።
፲፭ ከሰባትም ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ ይልቅ ፡ ለአንቺ ፡
ከምትሻል ፡ ከምትወድድሽ ፡ ምራት ፡ ተወል
ዶአልና ፡ ሰውነትሽን ፡ ያሳድሰዋል ፥ በእርጅና
፲፮ ሽም ፡ ይመግብሻል ፡ አሉአት ። ኑኃሚንም ፡

ሕፃኑን ፡ ወሰደች ፡ አቀፈችውም ÷ ሞግዚትም ፡
፲፯፡ ሆነችው ። ሴቶችም ፡ ጎረቤቶችዋ ፦ ለኑኃሚን ፡
ወንድ ፡ ልጅ ፡ ተወለደላት ፡ እያሉ ፡ ስም ፡ አወ
ጡለት ፤ ስሙንም ፡ ኢዮቤድ ፡ ብለው ፡ ጠሩት ።
እርሱም ፡ የዳዊት ፡ አባት ፡ የእሴይ ፡ አባት ፡ ነው ።
፲፰፡ የፋሬስም ፡ ትውልድ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ፋሬስ ፡
ኤስሮምን ፡ ወለደ ÷ ኤስሮምም ፡ አራምን ፡ ፲፱፡
ወለደ ÷ አራምም ፡ አሚናዳብን ፡ ወለደ ÷ አሚ ፳፡
ናዳብም ፡ ነአሶንን ፡ ወለደ ÷ ነአሶንም ፡ ሰል
ሞንን ፡ ወለደ ÷ ሰልሞንም ፡ በዔዝን ፡ ወለደ ÷ ፳፩፡
በዔዝም ፡ ኢዮቤድን ፡ ወለደ ÷ ኢዮቤድም ፡ ፳፪፡
እሴይን ፡ ወለደ ÷ እሴይም ፡ ዳዊትን ፡ ወለደ ።

# መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ቀዳማዊ ።

( እርሱም ፡ መጽሐፈ ፡ ነገሥት ፡ ቀዳማዊ ፡ ነው ። )

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፡ በተራራማው ፡ በኤፍሬም ፡ አገር ፡ ከአርማ
ቴም ፡ መሴፋ ፡ የሆነ ፡ ስሙ ፡ ሕልቃና ፡ የተባለ ፡
ኤፍሬማዊ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ እርሱም ፡ የኢያሬም
ኤል ፡ ልጅ ፡ የኢሊዮ ፡ ልጅ ፡ የቶሑ ፡ ልጅ ፡
፪፡ የናሲብ ፡ ልጅ ፡ ነበረ ። ሁለትም ፡ ሚስቶች ፡
ነበሩት ፤ የአንዲቱ ፡ ስም ፡ ሐና ፡ የሁለተኛይ
ቱም ፡ ስም ፡ ፍናና ፡ ነበረ ፤ ለፍናናም ፡ ልጆች ፡
ነበሩአት ÷ ለሐና ፡ ግን ፡ ልጅ ፡ አልነበራትም ።
፫፡ ያም ፡ ሰው ፡ በሴሎ ፡ ይሰግድ ፡ ዘንድ ፡ ለሠራ
ዊት ፡ ጌታም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይሠዋ ፡ ዘንድ ፡
ከከተማው ፡ በየዓመቱ ፡ ይወጣ ፡ ነበር ። የእግ
ዚአብሔርም ፡ ካህናት ፡ ሁለቱ ፡ የዔሊ ፡ ልጆች ፡
፬፡ አፍኒንና ፡ ፊንሐስ ፡ በዚያ ፡ ነበሩ ። ሕልቃና ፡
የሚሠዋበት ፡ ቀን ፡ በደረሰ ፡ ጊዜም ፡ ለሚስቱ ፡
ለፍናና ፡ ለወንዶችና ፡ ለሴቶች ፡ ልጆችዋ ፡ ሁሉ ፡
፭፡ እድል ፡ ፈንታቸውን ፡ ሰጣቸው ። ሐናንም ፡ ይወ
ድድ ፡ ነበርና ፡ ለሐና ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ እድል ፡
ፈንታ ፡ ሰጣት ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ማኅፀን
፮፡ ዋን ፡ ዘግቶ ፡ ነበር ። እግዚአብሔርም ፡ ማኅፀ
ንዋን ፡ ዘግቶ ፡ ነበርና ፡ ጣውንትዋ ፡ ታስቈጣት ፡
፯፡ ታበሳጫትም ፡ ነበር ። በየዓመቱም ፡ እንዲህ ፡
በደረገ ፡ ጊዜ ፡ እርስዋም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
በምትወጣበት ፡ ጊዜ ፡ ታበሳጫት ፡ ነበር ፤
ሐናም ፡ ታለቅስ ፡ ነበር ÷ አንዳችም ፡ አትቀም
፰፡ ስም ፡ ነበር ። ባልዋም ፡ ሕልቃና ፡— ሐና ፡
ሆይ ÷ ለምን ፡ ታለቅሻለሽ ? ለምንስ ፡ አትቀም
ሺም ? ለምንስ ፡ ልብሽ ፡ ያዝንብሻል ? እኔስ ፡
ከአሥር ፡ ልጆች ፡ አልሻልልሽምን ? አላት ።
፱፡ በሴሎ ፡ ከበሉና ፡ ከጠጡ ፡ በኋላም ፡ ሐና ፡
ተነሣች ። ካህኑም ፡ ዔሊ ፡ በእግዚአብሔር ፡
መቅደስ ፡ መቃን ፡ አጠገብ ፡ በመንበሩ ፡ ላይ ፡
፲፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ። እርስዋም ፡ በልብዋ ፡ ትመ
ረር ፡ ነበር ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ጸለየች ÷
፲፩፡ ጽኑ ፡ ልቅሶም ፡ አለቀሰች ። እርስዋም ፡—
አቤቱ ÷ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ሆይ ÷ የባሪያህን ፡
መዋረድ ፡ ተመልክተህ ፡ ብታስበኝ ÷ እኔንም ፡
ባትረሳ ÷ ለባሪያህም ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ብትሰጥ ÷
ዕድሜውን ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እሰጠዋ
ለሁ ÷ ምላጭም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ አይደርስም ፡
ብላ ፡ ስእለት ፡ ተሳለች ።

፲፪፡ ጸሎትዋንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ባበ
ዛች ፡ ጊዜ ፡ ዔሊ ፡ አፍዋን ፡ ይመለከት ፡ ነበር ።
፲፫፡ ሐናም ፡ በልብዋ ፡ ትናገር ፡ ነበር ፤ ድምፅዋም ፡
ሳይሰማ ፡ ከንፈርዋን ፡ ታንቀሳቅስ ፡ ነበር ፤
፲፬፡ ዔሊም ፡ እንደ ፡ ሰከረች ፡ ቈጠራት ። ዔሊም ፡—
ስካርሽ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ? የወይን ፡ ጠጅ
፲፭፡ ሽን ፡ ከአንቺ ፡ አርቂው ፡ አላት ። ሐናም ፡—
ጌታዬ ፡ ሆይ ÷ አይደለም ÷ እኔስ ፡ ልብዋ ፡ ያዘ
ነባት ፡ ሴት ፡ ነኝ ፤ ጠጅና ፡ ሌላ ፡ የሚያሰክር ፡
ነገር ፡ አልጠጣሁም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ በእግዚአብ
፲፮፡ ሔር ፡ ፊት ፡ ነፍሴን ፡ አፈሰስሁ ፤ ኀዘኔና ፡ ጭን
ቀቴ ፡ ስለ ፡ በዛ ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ ድረስ ፡ ተናግሬ
አለሁና ፡ ባሪያህን ፡ እንደ ፡ ምናምንቴ ፡ ሴት ፡ አት
፲፯፡ ቍጠረኝ ፡ ብላ ፡ መለሰችለት ። ዔሊም ፡— በደ
ኅና ፡ ሂጂ ÷ የእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ የለመን
ሽውን ፡ ልመና ፡ ይስጥሽ ፡ ብሎ ፡ መለሰላት ።
፲፰፡ እርስዋም ፡— ባሪያህ ፡ በዓይንህ ፡ ፊት ፡ ሞገስ ፡
ላግኝ ፡ አለች ። ሴቲቱም ፡ መንገድዋን ፡ ሄደች ፤
በላችም ÷ ፊትዋም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲያ ፡ አዘ
ንተኛ ፡ መስሎ ፡ አልታየም ።
፲፱፡ ማልደው ፡ ተነሥተው ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ሰገዱ ÷ ተመልሰውም ፡ ወደ ፡ አርማቴም ፡
ወደ ፡ ቤታቸው ፡ መጡ ። ሕልቃናም ፡ ሚስ
ቱን ፡ ሐናን ፡ አወቃት ፤ እግዚአብሔርም ፡
፳፡ አሰባት ፤ የመፅነስዋም ፡ ወራት ፡ ካለፈ ፡ በኋላ ፡
ሐና ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፤ እርስዋም ፡—
ከእግዚአብሔር ፡ ለምኜዋለሁ ፡ ስትል ፡ ስሙን ፡
ሳሙኤል ፡ ብላ ፡ ጠራችው ።
፳፩፡ ሰውዮውም ፡ ሕልቃና ፡ ከቤተ ፡ ሰቡ ፡ ሁሉ ፡
ጋር ፡ የዓመቱን ፡ መሥዋዕትና ፡ ስእለቱን ፡ ለእ
፳፪፡ ግዚአብሔር ፡ ያቀርብ ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ። ሐና ፡
ግን ፡ አልወጣችም ÷ ባልዋንም ፡— ሕፃኑ ፡
ጡት ፡ እስኪተው ፡ ድረስ ፡ እቀመጣለሁ ፤ ከዚ
ያም ፡ በኋላ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይታይ ፡
ዘንድ ÷ በዚያም ፡ ለዘላለም ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡
፳፫፡ አመጣዋለሁ ፡ አለችው ። ባልዋም ፡ ሕልቃና ፡—
በዓይንሽ ፡ ደስ ፡ ያሰኘሽን ፡ አድርጊ ÷ ጡትም ፡
እስኪተው ፡ ድረስ ፡ ተቀመጪ ፤ ብቻ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ቃሉን ፡ ያጽና ፡ አላት ። ሴቲቱም ፡
ልጅዋን ፡ እያጠባች ፡ ጡት ፡ እስኪተው ፡ ድረስ ፡
፳፬፡ በቤትዋ ፡ ተቀመጠች ። ጡትም ፡ በተወ ፡ ጊዜ ፡
ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ እርሱንና ፡ አንድ ፡ የሦስት ፡

ሕፃኑን ፡ ወሰደች ፡ አቀፈችውም ፥ ሞግዚትም ፡ ሆነችው ። ፲፯ ሴቶችም ፡ ጎረቤቶችዋ ፡ ለኑኃሚን ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ተወለደላት ፡ እያሉ ፡ ስም ፡ አወጡለት ፤ ስሙንም ፡ ኢዮቤድ ፡ ብለው ፡ ጠሩት ። እርሱም ፡ የዳዊት ፡ አባት ፡ የእሴይ ፡ አባት ፡ ነው ። ፲፰ የፋሬስም ፡ ትውልድ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ፋሬስ ፡ ኤስሮምን ፡ ወለደ ፥ ፲፱ ኤስሮምም ፡ አራምን ፡ ወለደ ፥ አራምም ፡ አሚናዳብን ፡ ወለደ ፥ ፳ አሚናዳብም ፡ ነአሶንን ፡ ወለደ ፥ ነአሶንም ፡ ሰልሞንን ፡ ወለደ ፥ ፳፩ ሰልሞንም ፡ ቦዔዝን ፡ ወለደ ፥ ቦዔዝም ፡ ኢዮቤድን ፡ ወለደ ፥ ፳፪ ኢዮቤድም ፡ እሴይን ፡ ወለደ ፥ እሴይም ፡ ዳዊትን ፡ ወለደ ።

# መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ቀዳማዊ ።

( እርሱም ፡ መጽሐፈ ፡ ነገሥት ፡ ቀዳማዊ ፡ ነው ። )

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ በተራራማው ፡ በኤፍሬም ፡ አገር ፡ ከአርማቴም ፡ መሴፋ ፡ የሆነ ፡ ስሙ ፡ ሕልቃና ፡ የተባለ ፡ ኤፍሬማዊ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ እርሱም ፡ የኢያሬምኤል ፡ ልጅ ፡ የኢሊዮ ፡ ልጅ ፡ የቶሑ ፡ ልጅ ፡ የናሲብ ፡ ልጅ ፡ ነበረ ። ፪ ሁለትም ፡ ሚስቶች ፡ ነበሩት ፤ የአንዲቱ ፡ ስም ፡ ሐና ፡ የሁለተኛይቱም ፡ ስም ፡ ፍናና ፡ ነበረ ፤ ለፍናናም ፡ ልጆች ፡ ነበሩአት ፥ ለሐና ፡ ግን ፡ ልጅ ፡ አልነበራትም ። ፫ ያም ፡ ሰው ፡ በሴሎ ፡ ይሰግድ ፡ ዘንድ ፡ ለሠራዊት ፡ ጌታም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይሠዋ ፡ ዘንድ ፡ ከከተማው ፡ በየዓመቱ ፡ ይወጣ ፡ ነበር ። የእግዚአብሔርም ፡ ካህናት ፡ ሁለቱ ፡ የዔሊ ፡ ልጆች ፡ አፍኒንና ፡ ፊንሐስ ፡ በዚያ ፡ ነበሩ ። ፬ ሕልቃና ፡ የሚሠዋበት ፡ ቀን ፡ በደረሰ ፡ ጊዜም ፡ ለሚስቱ ፡ ለፍናና ፡ ለወንዶችና ፡ ለሴቶች ፡ ልጆችዋ ፡ ሁሉ ፡ እድል ፡ ፈንታቸውን ፡ ሰጣቸው ። ፭ ሐናንም ፡ ይወድድ ፡ ነበርና ፡ ለሐና ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ ሰጣት ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ማኅፀንዋን ፡ ዘግቶ ፡ ነበር ። ፮ እግዚአብሔርም ፡ ማኅፀንዋን ፡ ዘግቶ ፡ ነበርና ፡ ጣውንትዋ ፡ ታስቈጣት ፡ ታበሳጫትም ፡ ነበር ። ፯ በየዓመቱም ፡ እንዲህ ፡ በደረገ ፡ ጊዜ ፡ እርስዋም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ በምትወጣበት ፡ ጊዜ ፡ ታበሳጫት ፡ ነበር ፤ ሐናም ፡ ታለቅስ ፡ ነበር ፥ አንዳችም ፡ አትቀምስም ፡ ነበር ። ፰ ባልዋም ፡ ሕልቃና ፦ ሐና ፡ ሆይ ፥ ለምን ፡ ታለቅሻለሽ ? ለምንስ ፡ አትቀምሺም ? ለምንስ ፡ ልብሽ ፡ ያዝንብሻል ? እኔስ ፡ ከአሥር ፡ ልጆች ፡ አልሻልልሽምን ? አላት ።

፱ በሴሎ ፡ ከበሉና ፡ ከጠጡ ፡ በኋላም ፡ ሐና ፡ ተነሣች ። ካህኑም ፡ ዔሊ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ መቃን ፡ አጠገብ ፡ በመንበሩ ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ። ፲ እርስዋም ፡ በልብዋ ፡ ተመረር ፡ ነበር ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ጸለየች ፥ ጽኑ ፡ ልቅሶም ፡ አለቀሰች ። ፲፩ እርስዋም ፦ አቤቱ ፥ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፥ የባሪያህን ፡ መዋረድ ፡ ተመልክተህ ፡ ብታስበኝ ፥ እኔንም ፡ ባትረሳ ፥ ለባሪያህም ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ብትሰጥ ፥ ዕድሜውን ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እሰጠዋለሁ ፥ ምላጭም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ አይደርስም ፡ ብላ ፡ ስእለት ፡ ተሳለች ።

፲፪ ጸሎትዋንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ባበዛች ፡ ጊዜ ፡ ዔሊ ፡ አፍዋን ፡ ይመለከት ፡ ነበር ። ፲፫ ሐናም ፡ በልብዋ ፡ ትናገር ፡ ነበር ፤ ድምፅዋም ፡ ሳይሰማ ፡ ከንፈርዋን ፡ ታንቀሳቅስ ፡ ነበር ፤ ዔሊም ፡ እንደ ፡ ሰከረች ፡ ቈጠራት ። ፲፬ ዔሊም ፦ ስካርሽ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ? የወይን ፡ ጠጅሽን ፡ ከአንቺ ፡ አርቂው ፡ አላት ። ፲፭ ሐናም ፦ ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ አይደለም ፥ እኔስ ፡ ልብዋ ፡ ያዘነባት ፡ ሴት ፡ ነኝ ፤ ጠጅና ፡ ሌላ ፡ የሚያሰክር ፡ ነገር ፡ አልጠጣሁም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ነፍሴን ፡ አፈሰስሁ ፤ ፲፮ ኀዘኔና ፡ ጭንቀቴ ፡ ስለ ፡ በዛ ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ ድረስ ፡ ተናግሬአለሁና ፡ ባሪያህን ፡ እንደ ፡ ምናምንቴ ፡ ሴት ፡ አትቍጠረኝ ፡ ብላ ፡ መለሰችለት ። ፲፯ ዔሊም ፦ በደኅና ፡ ሂጂ ፥ የእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ የለመንሽውን ፡ ልመና ፡ ይስጥሽ ፡ ብሎ ፡ መለሰላት ። ፲፰ እርስዋም ፦ ባሪያህ ፡ በዓይንህ ፡ ፊት ፡ ሞገስ ፡ ላግኝ ፡ አለች ። ሴቲቱም ፡ መንገድዋን ፡ ሄደች ፤ በላችም ፥ ፊትዋም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲያ ፡ አዘንተኛ ፡ መስሎ ፡ አልታየም ።

፲፱ ማልደው ፡ ተነሥተው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሰገዱ ፥ ተመልሰውም ፡ ወደ ፡ አርማቴም ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ መጡ ። ሕልቃናም ፡ ሚስቱን ፡ ሐናን ፡ አወቃት ፤ እግዚአብሔርም ፡ አሰባት ፤ ፳ የመፅነስዋም ፡ ወራት ፡ ከለፈ ፡ በኋላ ፡ ሐና ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፤ እርስዋም ፦ ከእግዚአብሔር ፡ ለምኜዋለሁ ፡ ስትል ፡ ስሙን ፡ ሳሙኤል ፡ ብላ ፡ ጠራችው ።

፳፩ ሰውዮውም ፡ ሕልቃና ፡ ከቤተ ፡ ሰቡ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ የዓመቱን ፡ መሥዋዕትና ፡ ስእለቱን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያቀርብ ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ። ፳፪ ሐና ፡ ግን ፡ አልወጣችም ፥ ባልዋንም ፦ ሕፃኑ ፡ ጡት ፡ እስኪተው ፡ ድረስ ፡ እቀመጣለሁ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይታይ ፡ ዘንድ ፥ በዚያም ፡ ለዘላለም ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ አመጣዋለሁ ፡ አለችው ። ፳፫ ባልዋም ፡ ሕልቃና ፦ በዓይንሽ ፡ ደስ ፡ ያሰኘሽን ፡ አድርጊ ፥ ጡትም ፡ እስኪተው ፡ ድረስ ፡ ተቀመጪ ፤ ብቻ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃሉን ፡ ያጽና ፡ አላት ። ሴቲቱም ፡ ልጅዋን ፡ እያጠባች ፡ ጡት ፡ እስኪተው ፡ ድረስ ፡ በቤትዋ ፡ ተቀመጠች ። ፳፬ ጡትም ፡ በተወ ፡ ጊዜ ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ እርሱንና ፡ አንድ ፡ የሦስት ፡

ዓመት ፡ ወይፈን ÷ አንድ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ ዱቄት ÷ አንድ ፡ አቁማዳ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ይዛ ፡ ወደ ፡ ሴሎ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አመጣችው ፤ ሕፃኑም ፡ ገና ፡ ታናሽ ፡ ነበረ ። ፳፭ ወይፈኑንም ፡ አረዱ ÷ ሕፃኑንም ፡ ወደ ፡ ዔሊ ፡ አመጡት ። ፳፮ እርስዋም ፡ አለች ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ÷ በሕያው ፡ ነፍስህ ፡ እምላለሁ ! ጌታ ፡ ሆይ ÷ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለመጸለይ ፡ በዚህ ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ቆማ ፡ የነበረች ፡ ሴት ፡ እኔ ፡ ነኝ ። ፳፯ ስለዚህ ፡ ሕፃን ፡ ጸለይሁ ፤ እግዚአብሔርም ፡ የለመንሁትን ፡ ልመናዬን ፡ ሰጥቶኛል ፤ ፳፰ እኔም ፡ ደግሞ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰጥቼዋለሁ ፤ ዕድሜ ውን ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተሰጠ ፡ ይሆ ናል ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ሐናም ፡ ስትጸልይ ፡ እንዲህ ፡ አለች ፡ —
ልቤ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጸና ÷
ቀንዴ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ፤
አፌ ፡ በጠላቶቼ ፡ ላይ ፡ ተከፈተ ፤
በማዳንህ ፡ ደስ ፡ ብሎኛል ።
፪ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቅዱስ ፡ የለምና ÷
እንደ ፡ አምላካችንም ፡ ጻድቅ ፡ የለምና ፤
ከአንተ ፡ በቀር ፡ ቅዱስ ፡ የለም ።
፫ አትታበዩ ÷ በኵራትም ፡ አትናገሩ ፤
እግዚአብሔር ፡ አዋቂ ፡ ነውና ÷
እግዚአብሔርም ፡ ሥራውን ፡ የሚመዝን ፡ ነውና ፤
ከአፋችሁ ፡ የኵራት ፡ ነገር ፡ አይውጣ ።
፬ የኃያላንን ፡ ቀስት ፡ ሰብሮአል ÷
ደካሞችም ፡ በኃይል ፡ ታጥቀዋል ።
፭ ጠግበው ፡ የነበሩ ፡ እንጀራ ፡ አጡ ፤
ተርበው ፡ የነበሩ ፡ ከራብ ፡ ዐርፈዋል ፤
መካኒቱ ፡ ሰባት ፡ ወልዳለችና ÷
ብዙም ፡ የወለደችው ፡ ደከማለች ።
፮ እግዚአብሔር ፡ ይገድላል ፡ ያድናልም ፤
ወደ ፡ ሲኦል ፡ ያወርዳል ÷ ያወጣል ።
፯ እግዚአብሔር ፡ ድሀ ፡ ያደርጋል ÷ ባለጠጋም ፡ ያደርጋል ፤
ያዋርዳል ÷ ደግሞም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ።
፰ ከሕዝቡ ፡ መኳንንት ፡ ጋር ፡ ያስቀምጣቸው ፡ ዘንድ ÷
የክብርንም ፡ ዙፋን ፡ ያወርሳቸው ፡ ዘንድ ÷
ችግረኛውን ፡ ከመሬት ፡ ያስነሣል ÷
ምስኪኑንም ፡ ከጕድፍ ፡ ያስነሣል ፤
የምድር ፡ መሠረቶች ፡ የእግዚአብሔር ፡ ናቸውና ÷
በእነርሱ ፡ ላይም ፡ ዓለምን ፡ አደረገ ።
፱ እርሱ ፡ የቅዱሳኑን ፡ እግር ፡ ይጠብቃል ፡
ኃጥአን ፡ ግን ፡ ዝም ፡ ብለው ፡ በጨለማ ፡ ይቀመጣሉ ፤
ሰው ፡ በኃይሉ ፡ አይበረታምና ።
፲ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ የሚጣሉ ፡ ይደቀቃሉ ፤
በሰማይም ፡ ያንጐደጕድባቸዋል ፤
እግዚአብሔር ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ይፈርዳል ፤
ለንጉሡም ፡ ኃይል ፡ ይሰጣል ፤
የመሲሑንም ፡ ቀንድ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ።

፲፩ ሕልቃናም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ወደ ፡ አርማቴም ፡ ሄደ ፤ ብላቴናውም ፡ በካህኑ ፡ በዔሊ ፡ ፊት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያገለግል ፡ ነበር ።

፲፪ የዔሊም ፡ ልጆች ፡ ምናምንቴዎች ፡ ነበሩ ፤ እግዚአብሔርንም ፡ አያውቁም ፡ ነበር ። ፲፫ የካህ ናትም ፡ ልማድ ፡ በሕዝቡ ፡ ዘንድ ፡ እንዲህ ፡ ነበረ ፤ ሰው ፡ ሁሉ ፡ መሥዋዕት ፡ ሲያቀርብ ፡ ሥጋው ፡ በተቀቀለ ፡ ጊዜ ፡ የካህኑ ፡ ሎሌ ፡ ይመጣ ፡ ነበር ÷ በእጁም ፡ ሦስት ፡ ጣት ፡ ያለው ፡ ሜንጦ ፡ ነበረ ፤ ፲፬ ወደ ፡ ድስቱም ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ ምንቸቱ ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ አፍላሉ ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ ቶፋው ፡ ይሰድደው ፡ ነበር ፤ ሜንጦውም ፡ ያወጣውን ፡ ሁሉ ፡ ካህኑ ፡ ለእርሱ ፡ ይወስደው ፡ ነበር ። ወደዚያም ፡ በመጡት ፡ በእስራኤላው ያን ፡ ላይ ፡ በሴሎ ፡ እንዲህ ፡ ያደርጉ ፡ ነበር ። ፲፭ ደግሞም ፡ ስቡን ፡ ሳያቃጥሉ ፡ የካህኑ ፡ ሎሌ ፡ መጥቶ ፡ የሚሠዋውን ፡ ሰው ፡— ጥሬውን ፡ እንጂ ፡ የተቀቀለውን ፡ ሥጋ ፡ ከአንተ ፡ አይወስድምና ፡ እጠብስለት ፡ ዘንድ ፡ ለካህኑ ፡ ሥጋ ፡ ስጠኝ ፡ ይለው ፡ ነበር ። ፲፮ ሰውዮውም ፡— አስቀ ድሞ ፡ ስቡን ፡ ያቃጥሉት ፡ ኋላም ፡ ሰውነትህ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኛትን ፡ ትወስዳለህ ፡ ቢለው ÷ እርሱ ፡— አይሆንም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ አሁን ፡ ስጠኝ ፤ እንቢም ፡ ብትል ፡ በግድ ፡ እወስደዋለሁ ፡ ይለው ፡ ነበር ። ፲፯ ሰዎቹም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቍርባን ፡ ይንቁ ፡ ነበርና ፡ የጐበዛዝቱ ፡ ኃጢአት ፡ በእግ ዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ነበረች ።

፲፰ ሳሙኤል ፡ ግን ፡ ገና ፡ ብላቴና ፡ ሳለ ፡ የበፍታ ፡ ኤፉድ ፡ ለብሶ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያገለ ግል ፡ ነበር ። ፲፱ እናቱም ፡ ታናሽ ፡ መደረቢያ ፡ ሠራችለት ÷ በየዓመቱም ፡ መሥዋዕት ፡ ለመ ሠዋት ፡ ከባልዋ ፡ ጋር ፡ ስትወጣ ፡ ታመጣለት ፡ ነበር ። ፳ ዔሊም ፡ ሕልቃናንና ፡ ሚስቱን ፡— ለእ ግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ተሳለችው ፡ ስጦታ ፡ ፋንታ ፡ ከዚህች ፡ ሴት ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘር ፡ ይስጥህ ፡ ብሎ ፡ ባረካቸው ፤ እነርሱም ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ ሄዱ ። ፳፩ እግዚአብሔርም ፡ ሐናን ፡ አሰበ ÷ ፀነሰ ችም ÷ ሦስት ፡ ወንዶችና ፡ ሁለትም ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ወለደች ። ብላቴናውም ፡ ሳሙኤል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አደገ ።

፳፪ ዔሊም ፡ እጅግ ፡ አረጀ ፤ ልጆቹም ፡ በእስራ ኤል ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያደረጉትን ፡ ሁሉ ÷ በመገናኛ ውም ፡ ድንኳን ፡ ደጅ ፡ ከሚያገለግሉት ፡ ሴቶች ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ተኙ ፡ ሰማ ። ፳፫ እርሱም ፡ አላቸው ፡— ስለ ፡ ክፉ ፡ ሥራችሁ ፡ ከዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ሰምቻለሁና ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ታደርጋላችሁ ? ፳፬ ልጆቼ ፡ ሆይ ÷ የእግዚአብሔ

ርን፡ ሕዝብ ፡ ኃጢአተኛ ፡ በማድረጋችሁ፡ ስለ፡
እናንተ ፡ የደረሰኝ ፡ ወሬ ፡ መልካም ፡ አይደለ
፳፭ ምና ፡ ይህ ፡ አይሆንም ። ሰውስ ፡ ሰውን ፡ ቢበ
ድል ፡ እግዚአብሔር ፡ ይፈርድበታል ፤ ሰው ፡
ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ቢበድል ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡
የሚለምን ፡ ማን ፡ ነው ? እነርሱ ፡ ግን ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ሊገድላቸው ፡ ወድዶአልና ፡ የአባታ
፳፮ ቸውን ፡ ቃል ፡ አልሰሙም ። ብላቴናውም ፡
ሳሙኤል ፡ እያደገ ፡ ሄደ ፤ በእግዚአብሔርም ፡
በሰውም ፡ ፊት ፡ ሞገስ ፡ እያገኘ ፡ ሄደ ።

፳፯ የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ዔሊ ፡ መጥቶ ፡
አለው ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
በግብጽ ፡ በፈርዖን ፡ ቤት ፡ ባሪያ ፡ ሳለ ፡ ለአባ
፳፰ ትህ ፡ ቤት ፡ ተገለጥሁ ፤ ከእስራኤልም ፡ ነገድ ፡
ሁሉ ፡ ካህን ፡ ይሆነኝ ፡ ዘንድ ÷ በመሠዊያዬ ፡
ላይ ፡ ይሠዋ ፡ ዘንድ ÷ ዕጣንንም ፡ ያጥን ፡ ዘንድ ÷
ኤፉድንም ፡ በፊቴ ፡ ይለብስ ፡ ዘንድ ፡ ለእኔ ፡
መረጥሁት ፤ የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ የእሳት ፡
ቍርባን ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ምግብ ፡ ለአባትህ ፡ ቤት ፡
፳፱ ሰጠሁ ። በማደሪያዬ ፡ ያቀርቡት ፡ ዘንድ ፡ ያዘ
ዝሁትን ፡ መሥዋዕቴንና ፡ ቍርባኔን ፡ ስለ ፡ ምን ፡
ረገጣችሁ ? እንድትወፍሩም ፡ የሕዝቤን ፡ የእ
ስራኤልን ፡ ቍርባን ፡ ሁሉ ፡ መጀመሪያ ፡ በመ
ብላታችሁ ፡ ከእኔ ፡ ይልቅ ፡ ልጆችህን ፡ ለምን ፡
፴ አከበርህ ? ስለዚህም ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በእውነት ፡
ቤትህ ፡ የአባትህም ፡ ቤት ፡ ለዘላለም ፡ በፊቴ ፡
እንዲኖር ፡ ተናግሬአለሁ ፤ አሁን ፡ ግን ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ያከበሩኝን ፡ አከ
ብራለሁና ÷ የናቁኝም ፡ ይናቃሉና ፡ ይህ ፡ አይ
፴፩ ሆንልኝም ። እነሆ ÷ ለቤትህ ፡ ሽማግሌ ፡ እንዳ
ይገኝ ÷ ክንድህን ፡ የአባትህንም ፡ ቤት ፡ ክንድ ፡
፴፪ የምሰብርበት ፡ ዘመን ፡ ይመጣል ። በእስራኤል ፡
በረከት ፡ ሁሉ ÷ በማደሪያዬ ፡ ጠላትህን ፡ ታያ
ለህ ፤ በቤትህም ፡ ለዘላለም ፡ ሽማግሌ ፡ አይገ
፴፫ ኝም ። ከመሠዊያዬ ፡ ያልተቈረጠ ፡ ልጅህ ፡
ቢገኝ ፡ ዓይንህን ፡ ያፈዝዘዋል ÷ ነፍስህንም ፡ ያሳ
ዝናል ፡ ከቤትህም ፡ የሚወለዱ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
፴፬ በጕልማስነት ፡ ይሞታሉ ። ይህ ፡ በሁለቱ ፡ ልጆ
ችህ ፡ በአፍኒንና ፡ በፊንሐስ ፡ ላይ ፡ የሚመጣ ፡
ለአንተ ፡ ምልክት ፡ ነው ፤ ሁለቱ ፡ በአንድ ፡ ቀን ፡
፴፭ ይሞታሉ ። የታመነም ፡ ካህን ፡ ለእኔ ፡ አስነሣ
ለሁ ÷ በልቤም ፡ በነፍሴም ፡ እንዳለ ፡ እንዲሁ ፡
ያደርጋል ፤ እኔም ፡ የታመነ ፡ ቤት ፡ እሠራለታ
ለሁ ÷ ዘመኑን ፡ ሁሉ ፡ እኔ ፡ በቀባሁት ፡ ሰው ፡
፴፮ ፊት ፡ ይሄዳል ። ከቤትህም ፡ የቀረው ፡ ሁሉ ፡
ይመጣል ÷ በፊቱም ፡ ሰግዶ ፡— ቍራሽ ፡ እን
ጀራ ፡ እበላ ፡ ዘንድ ፡ ከካህናት ፡ ወደ ፡ አንዲቱ ፡
ዕጣ ÷ እባክህ ÷ ስደደኝ ፡ ብሎ ፡ አንድ ፡ ብር ፡
አንድ ፡ እንጀራም ፡ ይለምናል ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ብላቴናውም ፡ ሳሙኤል ፡ በዔሊ ፡ ፊት ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ ያገለግል ፡ ነበር ፤ በዚያም ፡ ዘመን ፡
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ብርቅ ፡ ነበረ ፤ ራእ
፪ ይም ፡ አይገለጥም ፡ ነበር ። በዚያም ፡ ዘመን ፡
እንዲህ ፡ ሆነ ፤ የዔሊ ፡ ዓይኖች ፡ ማየት ፡ እስ
ኪሳናቸው ፡ ድረስ ፡ መፍዘዝ ፡ ጀምረው ፡ ነበር ።
፫ ዔሊም ፡ በስፍራው ፡ ተኝቶ ፡ ሳለ ÷ የእግዚአብ
ሔርም ፡ መብራት ፡ ገና ፡ ሳይጠፋ ÷ ሳሙኤልም ፡
የእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ባለበት ፡ በእግዚአ
፬ ብሔር ፡ መቅደስ ፡ ተኝቶ ፡ ሳለ ÷ እግዚአብሔር ፡
ሳሙኤልን ፡ ጠራው ፤ እርሱም ፡ — እነሆኝ ፡
፭ አለ ። ወደ ፡ ዔሊም ፡ ሮጠ ፡— እነሆኝ ፡ የጠራ
ኸኝ ፡ አለው ። እርሱም ፡ — አልጠራሁህም ፤
ተመልሰህ ፡ ተኛ ፡ አለው ። ሄዶም ፡ ተኛ ።
፮ እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፡— ሳሙኤል ፡ ሆይ ፡
ብሎ ፡ ጠራው ። ሳሙኤልም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡
ዔሊ ፡ ሄደና ፡— እነሆኝ ፡ የጠራኸኝ ፡ አለ ።
እርሱም ፡— ልጄ ፡ ሆይ ÷ አልጠራሁህም ፤ ተመ
፯ ልሰህ ፡ ተኛ ፡ ብሎ ፡ መለሰ ። ሳሙኤል ፡ ግን ፡
ገና ፡ እግዚአብሔርን ፡ አላወቀም ፡ ነበር ÷ የእ
ግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ገና ፡ አልተገለጠለትም ፡
፰ ነበር ። እግዚአብሔርም ፡ ሳሙኤልን ፡ እንደ ፡
ገና ፡ ሦስተኛ ፡ ጊዜ ፡ ጠራው ። እርሱም ፡ ተነ
ሥቶ ፡ ወደ ፡ ዔሊ ፡ ሄደና ፡— እነሆኝ ፡ የጠራ
ኸኝ ፡ አለ ። ዔሊም ፡ እግዚአብሔር ፡ ብላቴና
፱ ውን ፡ እንደ ፡ ጠራው ፡ አስተዋለ ። ዔሊም ፡
ሳሙኤልን ፡ — ሄደህ ፡ ተኛ ፤ ቢጠራህም ፡ —
አቤቱ ÷ ባሪያህ ፡ ይሰማልና ፡ ተናገር ፡ በለው ፡
አለው ። ሳሙኤልም ፡ ሄዶ ፡ በስፍራው ፡ ተኛ ።
፲ እግዚአብሔርም ፡ መጥቶ ፡ ቆመ ÷ እንደ ፡ ቀድ
ሞውም ፡— ሳሙኤል ፡ ሳሙኤል ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።
ሳሙኤልም ፡— ባሪያህ ፡ ይሰማልና ፡ ተናገር ፡
፲፩ አለ ። እግዚአብሔርም ፡ ሳሙኤልን ፡ አለው ፡—
እነሆ ÷ የሰማውን ፡ ሁሉ ፡ ሁለቱ ፡ ጆሮቹ ፡ ጭው ፡
የሚያደርግ ፡ አንድ ፡ ነገርን ፡ በእስራኤል ፡ አደ
፲፪ ርጋለሁ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ በቤቱ ፡ ላይ ፡ የተና
ገርሁትን ፡ ሁሉ ፡ በዔሊ ፡ አወርዳለሁ ፤ እኔም ፡
፲፫ ጀምሬ ፡ እፈጽምበታለሁ ። ልጆቹ ፡ የእርግ
ማን ፡ ነገር ፡ እንዳደረጉ ፡ አውቆ ፡ አልከለከላቸ
ውምና ፡ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ በቤቱ ፡ ለዘላለም ፡
፲፬ እንድፈርድ ፡ አስታውቄዋለሁ ። ስለዚህም ፡
የዔሊ ፡ ቤት ፡ ኃጢአት ፡ በመሥዋዕትና ፡ በቍ
ርባን ፡ ለዘላለም ፡ እንዳይሰረይለት ፡ ለዔሊ ፡
ቤት ፡ ምያለሁ ።

፲፭ ሳሙኤልም ፡ እስኪነጋ ፡ ተኛ ÷ ማልዶም ፡
ተነሥቶ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ደጅ ፡ ከፈተ ።
ሳሙኤልም ፡ ራእዩን ፡ ለዔሊ ፡ መንገር ፡ ፈራ ።
፲፮ ዔሊም ፡ ሳሙኤልን ፡ ጠርቶ ፡— ልጄ ፡ ሳሙ
ኤል ፡ ሆይ ÷ አለ ፤ እርሱም ፡— እነሆኝ ፡ አለ ።
፲፯ እርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡ የነገረህ ፡ ነገር ፡
ምንድር ፡ ነው ? ከእኔ ፡ አትሸሽግ ፤ ከነገረህ ፡
ነገር ፡ ሁሉ ፡ የሸሸግኸኝ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ እንዲህ ፡ ያድርግብህ ÷ እንዲህም ፡
፲፰ ይጨምርብህ ፡ አለው ። ሳሙኤልም ፡ ነገሩን ፡
ሁሉ ፡ ነገረው ÷ አንዳችም ፡ አልሸሸገውም ።
ዔሊም ፡— እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ፤ ደስ ፡

ያሰኘውን ፡ ያድርግ ፡ አለ ።
፲፱ ሳሙኤልም ፡ አደገ ÷ እግዚአብሔርም ፡ ከእ
ርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፤ ከቃሉም ፡ አንዳች ፡ በም
፳ ድር ፡ ላይ ፡ አይወድቀም ፡ ነበር ። እስራኤልም ፡
ሁሉ ፡ ከዳን ፡ እስከ ፡ ቤርሳቤህ ፡ ድረስ ፡ ሳሙ
ኤል ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ነቢይ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡
፳፩ የታመነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አወቀ ። እግዚአብሔ
ርም ፡ ደግሞ ፡ በሴሎ ፡ ተገለጠ ፤ እግዚአብሔ
ርም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ለሳሙኤል ፡
በሴሎ ፡ ይገለጥ ፡ ነበር ። የሳሙኤልም ፡ ቃል ፡
ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ደረሰ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ እስራኤልም ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ ጋር ፡
ሊዋጉ ፡ ወጡ ÷ በአቤንኤዘር ፡ አጠገብ ፡ ሰፈሩ ፤
፪ ፍልስጥኤማውያንም ፡ በአፌቅ ፡ ሰፈሩ ። ፍል
ስጥኤማውያንም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ተሰለፉ ፤
ሰልፉም ፡ በተመደበ ፡ ጊዜ ፡ እስራኤል ፡ በፍል
ስጥኤማውያን ፡ ፊት ፡ ተመቱ ፤ ጦርነት ፡ በተ
ደረገበትም ፡ ስፍራ ፡ ከእስራኤል ፡ አራት ፡ ሺህ ፡
፫ የሚያህሉ ፡ ሰዎችን ፡ ገደሉ ። ሕዝቡም ፡ ወደ ፡
ሰፈር ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ሽማግሌ
ዎች ፡— ዛሬ ፡ እግዚአብሔር ፡ በፍልስጥኤማ
ውያን ፡ ፊት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ መታን ? በመካከላ
ችን ፡ እንዲሄድ ÷ ከጠላቶቻችንም ፡ እጅ ፡ እን
ዲያድነን ÷ የእግዚአብሔርን ፡ የቃል ፡ ኪዳኑን ፡
፬ ታቦት ፡ ከሴሎ ፡ እናምጣ ፡ አሉ ። ሕዝቡም ፡
ወደ ፡ ሴሎ ፡ላኩ ÷ በኪሩቤልም ፡ ላይ ፡ የሚቀ
መጠውን ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ የቃል ፡ ኪዳኑን ፡ ታቦት ፡ ከዚያ ፡ አመጡ ፤
ሁለቱም ፡ የዔሊ ፡ ልጆች ፡ አፍኒንና ፡ ፊንሐስ ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ ጋር ፡
በዚያ ፡ ነበሩ ።
፭ የእግዚአብሔር ፡ የቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡
ወደ ፡ ሰፈር ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡
ታላቅ ፡ እልልታ ፡ አደረጉ ÷ ምድሪቱም ፡ አስተ
፮ ጋባች ። ፍልስጥኤማውያንም ፡ የእልልታውን ፡
ድምፅ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡— በዕብራውያን ፡ ሰፈር ፡
ያለው ፡ ይህ ፡ ታላቅ ፡ የእልልታ ፡ ድምፅ ፡ ምን
ድር ፡ ነው ? አሉ ። የእግዚአብሔርም ፡ ታቦት ፡
፯ ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ እንደ ፡ ገባ ፡ አስተዋሉ ። ፍልስ
ጥኤማውያንም ፡ ፈርተው ፡— እግዚአብሔር ፡
ወደ ፡ ሰፈር ፡ መጥቶአል ፡ አሉ ። ደግሞም ፡
እንዲህ ፡ አሉ ፡— ወዮልን ፤ ከዚህ ፡ አስቀድሞ ፡
፰ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ አልሆነም ። ወዮልን ፤ ከእነ
ዚህ ፡ ከኃያላን ፡ አማልክት ፡ እጅ ፡ ማን ፡ ያድነ
ናል ? እነዚህ ፡ አማልክት ፡ ግብጻውያንን ፡ በም
ድረ ፡ በዳ ፡ በልዩ ፡ በልዩ ፡ መቅሠፍት ፡ የመቱ ፡
፱ ናቸው ። እናንተ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ሆይ ÷
አይዞአችሁ ÷ ጐብዙ ፤ እናንተ ፡ ባሪያዎች ፡ እን
ዳደረጋችኋቸው ፡ ዕብራውያን ፡ ባሪያዎች ፡ እን
፲ ዳያደርጉአችሁ ፡ ጐብዙ ÷ ተዋጉ ። ፍልስጥኤ
ማውያንም ፡ ተዋጉ ፤ እስራኤልም ፡ ተመቱ ÷
ሁሉም ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ድንኳናቸው ፡ ሸሹ ፤
እጅግም ፡ ታላቅ ፡ ግድያ ፡ ሆነ ÷ ከእስራኤልም ፡
፲፩ ሠላሳ ፡ ሺህ ፡ እግረኞች ፡ ወደቁ ። የእግዚአብ
ሔርም ፡ ታቦት ፡ ተማረከች ÷ ሁለቱም ፡ የዔሊ ፡
ልጆች ፡ አፍኒንና ፡ ፊንሐስ ፡ ሞቱ ።
፲፪ በዚያም ፡ ቀን ፡ አንድ ፡ የብንያም ፡ ሰው ፡ ከሰ
ልፍ ፡ እየበረረ ፡ ልብሱን ፡ ቀድዶ ፡ በራሱም ፡
፲፫ ላይ ፡ ትቢያ ፡ ነስንሶ ፡ ወደ ፡ ሴሎ ፡ መጣ ። በመ
ጣም ፡ ጊዜ ፡ ዔሊ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡
ልቡ ፡ ተናውጦ ፡ ነበርና ፡ በመንገድ ፡ዳር ፡ በወ
ንበሩ ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ይጠባበቅ ፡ ነበር ፤ ሰው
ዮውም ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ ገብቶ ፡ በወራ ፡
ጊዜ ፡ ከተማይቱ ፡ ሁሉ ፡ ተጯጯኸች ።
፲፬ ዔሊም ፡ የጩኸቱን ፡ ድምፅ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡—
ይህ ፡ ጫጫታ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለ ። ሰውዮ
ውም ፡ ፈጥኖ ፡ መጣና ፡ ለዔሊ ፡ ነገረው ።
፲፭ ዔሊም ፡ የዘጠና ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡ ሽማግሌ ፡
ነበረ ፤ ዓይኖቹም ፡ ማየት ፡ እስኪሳናቸው ፡
፲፮ ድረስ ፡ ፈዝዘው ፡ ነበር ። ሰውዮውም ፡ ዔሊን ፡—
ከሰልፍ ፡ የመጣሁ ፡ እኔ ፡ ነኝ ÷ ዛሬም ፡ ከሰልፍ ፡
ኰበለልሁ ፡ አለ ። እርሱም ፡— ልጄ ፡ ሆይ ÷
፲፯ ነገሩሳ ፡ እንዴት ፡ ሆነ ? አለው ። ወሬኛውም ፡
መልሶ ፡— እስራኤል ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡
ፊት ፡ ሸሹ ፤ ደግሞ ፡ በሕዝቡ ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡
ግድያ ፡ ሆኖአል ÷ ሁለቱም ፡ ልጆችህ ፡ አፍኒ
ንና ፡ ፊንሐስ ፡ ሞተዋል ፤ የእግዚአብሔርም ፡
፲፰ ታቦት ፡ ተማርካለች ፡ አለ ። ሰውዮውም ፡ ስለ ፡
እግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ፡ ዔሊ ፡
በበሩ ፡ አጠገብ ፡ ካለው ፡ ከወንበሩ ፡ ወደቀ ፤
እርሱ ፡ ሽምግሎ ፡ ደንግዞም ፡ ነበርና ፡ አንገቱ ፡
ተሰብሮ ፡ ሞተ ። እርሱም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡
አርባ ፡ ዓመት ፡ ፈራጅ ፡ ነበረ ።
፲፱ ምራቱም ፡ የፊንሐስ ፡ ሚስት ፡ እርጉዝ ፡ ልት
ወልድ ፡ ተቃርባ ፡ ነበር ፤ የእግዚአብሔርም ፡
ታቦት ፡ እንደ ፡ ተማረከች ÷ አማትዋና ፡ ባል
ዋም ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡ በሰማች ፡ ጊዜ ፡ ምጥ ፡
፳ ደርሶባት ፡ ነበርና ፡ ተንበርክካ ፡ ወለደች ። ወደ ፡
ሞትም ፡ በቀረበች ፡ ጊዜ ፡ በዙሪያዋ ፡ ያሉት ፡
ሴቶች ፡— ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወልደሻልና ፡ አትፍሪ ፡
አሉአት ። እርስዋ ፡ ግን ፡ አልመለሰችላቸውም ÷
፳፩ በልብዋም ፡ አላኖረችውም ። እርስዋም ፡ የእ
ግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ስለ ፡ ተማረከች ፡ ስለ ፡
አማትዋና ፡ ስለ ፡ ባልዋም ፡— ክብር ፡ ከእስራ
ኤል ፡ ለቀቀ ፡ ስትል ፡ የሕፃኑን ፡ ስም ፡— ኢካ
፳፪ ቦድ ፡ ብላ ፡ ጠራችው ። እርስዋም ፡— የእግዚ
አብሔር ፡ ታቦት ፡ ተማርካለችና ፡ ክብር ፡ ከእ
ስራኤል ፡ ለቀቀ ፡ አለች ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ፍልስጥኤማውያንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ታቦት ፡ ወሰዱ ፤ ከአቤንኤዘርም ፡ ወደ ፡ አዛጦን ፡
፪ ይዘውት ፡ መጡ ። ፍልስጥኤማውያንም ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ወስደው ፡ ወደ ፡ ዳጎን ፡
ቤት ፡ አገቡት ÷ በዳጎንም ፡ አጠገብ ፡ አኖሩት ።
፫ በነጋውም ፡ የአዛጦን ፡ ሰዎች ፡ ማለዱ ÷ እነ

ሆም ፥ ዳጎን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በግምባሩ ፡ ወድቆ ፡ ነበር ፤ ዳጎንንም ፡ አንሥተው ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ መለሱት ።

፬ በነጋውም ፡ ማለዱ ፥ እነሆም ፥ ዳጎን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በግምባሩ ፡ ወድቆ ፡ ነበር ፤ የዳጎንም ፡ ራስ ፡ እጆቹም ፡ ተቈርጠው ፡ በመድረኩ ፡ ላይ ፡ ወድቀው ፡ ነበር ፤ የዳጎንም ፡ ደረት ፡ ብቻውን ፡ ቀርቶ ፡ ነበር ።

፭ ስለዚህም ፡ የዳጎን ፡ ካህናት ፡ ወደ ፡ ዳጎንም ፡ ቤት ፡ የሚገቡት ፡ ሁሉ ፡ በአዛጦን ፡ ያለውን ፡ የዳጎንን ፡ መድረክ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ አይረግጡም ።

፮ የእግዚአብሔርም ፡ እጅ ፡ በአዛጦን ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ከበደች ፥ አጠፋቸውም ፥ አዛጦንንና ፡ ድንበራቸውንም ፡ በእባጭ ፡ መታቸው ።

፯ የአዛጦንም ፡ ሰዎች ፡ እንዲህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፦ እጁ ፡ በእኛና ፡ በአምላካችን ፡ በዳጎን ፡ ላይ ፡ ጠንክራለችና ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ታቦት ፡ ከእኛ ፡ ዘንድ ፡ አይቀመጥ ፡ አሉ ።

፰ ልከውም ፡ የፍልስጥኤማውያንን ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ሰበሰቡና ፦ በእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ታቦት ፡ ምን ፡ እናድርግ ? አሉ ፤ እነርሱም ፦ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ታቦት ፡ ወደ ፡ ጌት ፡ ይዙር ፡ ብለው ፡ መለሱ ። የእስራኤልንም ፡ አምላክ ፡ ታቦት ፡ ወደዚያ ፡ ተሸከሙት ።

፱ ከተሸከሙትም ፡ በኋላ ፡ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ በታላቅ ፡ ድንጋጤ ፡ በከተማይቱ ፡ ላይ ፡ ሆነች ፤ ከታናሹም ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ድረስ ፡ የከተማይቱን ፡ ሰዎች ፡ መታ ፥ እባጭም ፡ መጣባቸው ።

፲ የእግዚአብሔርንም ፡ ታቦት ፡ ወደ ፡ አስቀሎና ፡ሰደዱት ። የእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ወደ ፡ አስቀሎና ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ አስቀሎናውያን ፦ እኛንና ፡ ሕዝባችንን ፡ ሊገድሉ ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ ታቦት ፡ አመጡብን ፡ ብለው ፡ ጮኹ ።

፲፩ በከተማይቱ ፡ ሁሉ ፡ የሞት ፡ ድንጋጤ ፡ ነበርና ፥ የእግዚአብሔርም ፡ እጅ ፡ በዚያ ፡ እጅግ ፡ ከብዳ ፡ ነበረችና ፡ ልከው ፡ የፍልስጥኤማውያንን ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ሰብስበው ፦ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ ታቦት ፡ ስደዱ ፥ እኛንና ፡ ሕዝባችንን ፡ እንዳይገድል ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ይመለስ ፡ አሉ ።

፲፪ ያልሞቱትም ፡ ሰዎች ፡ በእባጭ ፡ ተመቱ ፤ የከተማይቱም ፡ ዋይታ ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ወጣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ የእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ በፍልስጥኤማውያን ፡ አገር ፡ ሰባት ፡ ወር ፡ ተቀመጠ ።

፪ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ካህናትንና ፡ ምዋርተኞችን ፡ ጠርተው ፦ በእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ላይ ፡ ምን ፡ እናድርግ ? ወደ ፡ ስፍራውስ ፡ በምን ፡ እንሰደደው ? አስታውቁን ፡ አሉ ።

፫ እነርሱም ፦ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ ታቦት ፡ ብትሰድዱ ፡ የበደል ፡ መሥዋዕት ፡ መልሱለት ፡ እንጂ ፡ ባዶውን ፡ አትስደዱት ፥ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ትፈወሳላችሁ ፤ እጁም ፡ ከእናንተ ፡ አለመራቁ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ታውቃላችሁ ፡ አሉ ።

፬ እነርሱም ፦ ስለ ፡ በደል ፡ መሥዋዕት ፡ የምንመልስለት ፡ ምንድር ፡ ነው ? አሉ ። እነርሱም ፡ እንዲህ ፡ አሉ ፦ እናንተንና ፡ አለቆቻችሁን ፡ ያገኘች ፡ መቅሠፍት ፡ አንዲት ፡ ናትና ፡ እንደ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ አለቆች ፡ ቍጥር ፡ አምስት ፡ የወርቅ ፡ እባጮች ፡ አምስትም ፡ የወርቅ ፡ አይጦች ፡ አቅርቡ ።

፭ የእባጫችሁንም ፡ ምሳሌ ፥ ምድራችሁንም ፡ የሚያጠፋአትን ፡ የአይጦችን ፡ ምሳሌ ፡ አድርጋችሁ ፡ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ክብርን ፡ስጡ ፤ እጁን ፡ ከእናንተና ፡ ከአማልክቶቻችሁ ፡ ከምድራችሁም ፡ ምናልባት ፡ ያቀልል ፡ ይሆናል ።

፮ ግብጻውያንና ፡ ፈርዖንም ፡ ልባቸውን ፡ እንዳጸኑ ፡ ልባችሁን ፡ ለምን ፡ታጸናላችሁ ? እግዚአብሔር ፡ ኃይሉን ፡ ካደረገባቸው ፡ በኋላ ፡ ያወጡአቸው ፡ አይደሉምን ? እነርሱም ፡ አልሄዱምን ?

፯ አሁንም ፡ ወስዳችሁ ፡ አንዲት ፡ሰረገላ ፡ ሥሩ ፤ የሚያጠቡም ፥ ቀንበር ፡ ያልተጫነባቸውን ፡ ሁለት ፡ ላሞች ፡ በሰረገላ ፡ ጥመዱአቸው ፥ እንቦሶቻቸውንም ፡ ለይታችሁ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ መልሱአቸው ።

፰ የእግዚአብሔርንም ፡ ታቦት ፡ ወስዳችሁ ፡ በሰረገላው ፡ ላይ ፡ አኑሩት ፤ ስለ ፡ በደልም ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀረባችሁትን ፡ የወርቁን ፡ ዕቃ ፡ በሣጥን ፡ ውስጥ ፡ አድርጋችሁ ፡ በታቦቱ ፡ አጠገብ ፡ አኑሩት ፤ ይሄድም ፡ ዘንድ ፡ስደዱት ።

፱ ተመልከቱም ፤ በድንበሩም ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡ ቤትሳሚስ ፡ ቢወጣ ፡ ይህን ፡ እጅግ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ያደረገብን ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ፤ አለዚያም ፡ እንዳያው ፡ መጥቶብናል ፡ እንጂ ፡ የመታን ፡ የእርሱ ፡ እጅ ፡ እንዳልሆነ ፡ እናውቃለን ።

፲ ሰዎቹም ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ፤ የሚያጠቡትን ፡ ሁለቱን ፡ ላሞች ፡ ወሰዱ ፥ በሰረገላም ፡ ጠመዱአቸው ፥ እንቦሶቻቸውንም ፡ በቤት ፡ ዘጉባቸው ፤

፲፩ የእግዚአብሔርንም ፡ ታቦት ፥ የወርቁ ፡ አይጦችና ፡ የእባጮቻቸው ፡ ምሳሌ ፡ ያሉበትንም ፡ ሣጥን ፡ በሰረገላው ፡ ላይ ፡ ጫኑ ።

፲፪ ላሞችም ፡ ወደ ፡ ቤትሳሚስ ፡ ወደሚወስደው ፡ መንገድ ፡ አቅንተው ፡ እምቧ ፡ እያሉ ፡ በጐዳናው ፡ ላይ ፡ ሄዱ ፥ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ አላሉም ፤ የፍልስጥኤማውያንም ፡ አለቆች ፡ እስከ ፡ ቤትሳሚስ ፡ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ በኋላ ፡ በኋላቸው ፡ ይሄዱ ፡ ነበር ።

፲፫ የቤትሳሚስ ፡ ሰዎችም ፡ በሸለቆው ፡ ውስጥ ፡ ስንዴ ፡ ያጭዱ ፡ ነበር ፤ ዓይናቸውንም ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡ ታቦቱን ፡ አዩ ፥ በማየታቸውም ፡ ደስ ፡ አላቸው ።

፲፬ ሰረገላውም ፡ ወደ ፡ ቤትሳሚሳዊው ፡ ወደ ፡ ኢያሱ ፡ እርሻ ፡ መጣ ፥ ታላቅም ፡ ድንጋይ ፡ በነበረበት ፡ በዚያ ፡ ቆመ ፤ የሰረገላውንም ፡ እንጨት ፡ ፈልጠው ፡ ላሞቹን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረቡ ።

፲፭ ሌዋውያንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፥ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበረውንም ፡ የወርቅ ፡ ዕቃ ፡ ያለበትን ፡ ሣጥን ፡ አወረዱ ፥ በታላቁም ፡ ድንጋይ ፡

ላይ ፡ አኖሩት ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ የቤትሳሚስ ፡
ሰዎች ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥ
፲፮ ዋዕት ፡ አቀረቡ ፥ መሥዋዕትንም ፡ ሠዉ ። ፍል
ስጥኤማውያንም ፡ አምስቱ ፡ አለቆች ፡ ባዩት ፡
ጊዜ ፡ በዚያው ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ አስቀሎና ፡ ተመለሱ ።
፲፯ ፍልስጥኤማውያን ፡ ስለ ፡ በደል ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያቀረቡአቸው ፡ የወርቅ ፡
እባጮች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ አንዲቱ ፡ ለአዛጦን ፥
አንዲቱም ፡ ለጋዛ ፥ አንዲቱም ፡ ለአስቀሎና ፥
፲፰ አንዲቱ ፡ ለጌት ፥ አንዲቱ ፡ ለአቃሮን ፡ የወርቁም ፡
አይጦች ፡ ቍጥር ፡ ለአምስቱ ፡ የፍልስጥኤማው
ያን ፡ አለቆች ፡ እንደ ፡ ነበሩት ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡
ቍጥር ፡ እንዲሁ ፡ ነበረ ፤ እነርሱም ፡ እስከ ፡
ታላቁ ፡ ድንጋይ ፡ የሚደርሱ ፡ ከተሞችና ፡ መን
ደሮች ፡ ናቸው ። በዚህም ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ አስቀመጡ ፥ ድን
ጋዩም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በቤትሳሚሳዊው ፡
በኢያሱ ፡ እርሻ ፡ አለ ።
፲፱ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ታቦት ፡ ውስጥ ፡ ተመ
ልክተዋልና ፡ የቤትሳሚስን ፡ ሰዎች ፡ መታ ፤
በሕዝቡም ፡ ከአምስት ፡ ሺህ ፡ ሰው ፡ ሰባ ፡ ሰዎ
ችን ፡ መታ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ሕዝቡን ፡ በታ
ላቅ ፡ ግዳይ ፡ ስለ ፡ መታ ፡ ሕዝቡ ፡ አለቀሰ ።
፳ የቤትሳሚስም ፡ ሰዎች ፡— በዚህ ፡ በቅዱስ ፡ አም
ላክ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ መቆም ፡ ማን ፡
ይችላል ? ከእኛስ ፡ ወጥቶ ፡ ወደ ፡ ማን ፡ ይሄ
፳፩ ዳል ? አሉ ። በቂርያትይዓሪምም ፡ ወደ ፡ ተቀ
መጡት ፡ ሰዎች ፡ መልክተኞች ፡ ልከው ፡—
ፍልስጥኤማውያን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡
መልሰዋል ፤ ወርዳችሁም ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡
አውጡት ፡ አሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ የቂርያትይዓሪም ፡ ሰዎችም ፡ መጥተው ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ አወጡ ፥ በኮረብታ
ውም ፡ ላይ ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ አሚናዳብ ፡ ቤት ፡
አገቡት ፤ የእግዚአሔርንም ፡ ታቦት ፡ እንዲጠ
፪ ብቅ ፡ ልጁን ፡ አልዓዛርን ፡ ቀደሱት ። ታቦቱም ፡
በቂርያትይዓሪም ፡ ከተቀመጠበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡
ወራቱ ፡ ረዘመ ፥ ሀያ ፡ ዓመትም ፡ ሆነ ፤ የእስራ
ኤልም ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ አዝኖ ፡ እግዚአብሔርን ፡
ተከተለ ።
፫ ሳሙኤልም ፡ የእስራኤልን ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡—
በሙሉ ፡ ልባችሁ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከተ
መለሳችሁ ፡ እንግዶችን ፡ አማልክትና ፡ አስታ
ሮትን ፡ ከመካከላችሁ ፡ አርቁ ፥ ልባችሁንም ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አቅኑ ፥ እርሱንም ፡ ብቻ ፡
አምልኩ ፤ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ እጅ ፡ ያድ
፬ ናችኋል ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ። የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ በአሊምንና ፡ አስታሮትን ፡ አራቁ ፥
እግዚአብሔርንም ፡ ብቻ ፡ አመለኩ ።
፭ ሳሙኤልም ፡— እስራኤልን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡
ምጽጳ ፡ሰብስቡ ፥ ስለ ፡ እናንተም ፡ ወደ ፡ እግዚ
፮ አብሔር ፡ እጸልያለሁ ፡ አለ ። ወደ ፡ ምጽጳም ፡
ተሰበሰቡ ፤ ውኃም ፡ ቀድተው ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ፊት ፡ አፈሰሱ ፥ በዚያም ፡ ቀን ፡ ጾሙ ፥
በዚያም ፡— እግዚአብሔርን ፡ በድለናል ፡ አሉ ።
ሳሙኤልም ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ በም
፯ ጽጳ ፡ ፈረደ ። ፍልስጥኤማውያንም ፡ የእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ምጽጳ ፡ እንደ ፡ ተሰበሰቡ ፡
በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ የፍልስጥኤማውያን ፡ አለቆች ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ወጡ ፤ የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ ሰምተው ፡ ፍልስጥኤማውያንን ፡ ፈሩ ።
፰ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሳሙኤልን ፡— ከፍል
ስጥኤማውያን ፡ እጅ ፡ ያድነን ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡
አምላካችን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትጸልይ
፱ ልን ፡ ዘንድ ፡ አትታክት ፡ አሉት ። ሳሙኤልም ፡
አንድ ፡ የሚጠባ ፡ የበግ ፡ ጠቦት ፡ ወስዶ ፡ ለእግ
ዚአብሔር ፡ ፈጽሞ ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡
አድርጎ ፡ አቀረበው ፤ ሳሙኤልም ፡ ስለ ፡ እስራ
ኤል ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኸ ፥ እግዚአብ
፲ ሔርም ፡ ሰማው ። ሳሙኤልም ፡ የሚቃጠለ
ውን ፡ መሥዋዕት ፡ ሲያሳርግ ፡ ፍልስጥኤማው
ያን ፡ ከእስራኤል ፡ ጋር ፡ ሊዋጉ ፡ ቀረቡ ፤ እግ
ዚአብሔርም ፡ በዚያች ፡ ቀን ፡ በፍልስጥኤማ
ውያን ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ነጐድጓድ ፡ አንጐደጐደ ፥
አስደነገጣቸውም ፤ በእስራኤልም ፡ ፊት ፡ ድል ፡
፲፩ ተመቱ ። የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ከምጽጳ ፡
ወጡ ፥ ፍልስጥኤማውያንንም ፡ አሳደዱ ፤ በቤ
ትካር ፡ ታችም ፡ እስኪደርሱ ፡ ድረስ ፡ መቱአ
ቸው ።
፲፪ ሳሙኤልም ፡ አንድ ፡ ድንጋይ ፡ ወስዶ ፡ በም
ጽጳና ፡ በሼን ፡ መካከል ፡ አኖረው ፤ ስሙንም ፡—
እስከ ፡ አሁን ፡ ድረስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ረድ
ቶናል ፡ ሲል ፡ አቤንኤዘር ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።
፲፫ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ተዋረዱ ፥ ዳግመኛም ፡
ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ድንበር ፡ አል
ወጡም ፤ በሳሙኤል ፡ ዕድሜ ፡ ሁሉ ፡ የእግዚ
አብሔር ፡ እጅ ፡ በፍልስጥኤማውያን ፡ ላይ ፡ ነበ
፲፬ ረች ። ፍልስጥኤማውያንም ፡ ከአስቀሎና ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ጌት ፡ ድረስ ፡ ከእስራኤል ፡ የወ
ሰዱአቸው ፡ ከተሞች ፡ ለእስራኤል ፡ ተመለሱ ፤
እስራኤልም ፡ ድንበሩን ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡
እጅ ፡ አዳነ ። በእስራኤልና ፡ በአሞራውያንም ፡
መካከል ፡ ዕርቅ ፡ ነበረ ።
፲፭ ሳሙኤልም ፡ በዕድሜው ፡ ሁሉ ፡ በእስራ
፲፮ ኤል ፡ ላይ ፡ ይፈርድ ፡ ነበር ። በየዓመቱም ፡
ወደ ፡ ቤቴል ፡ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ ወደ ፡ ምጽጳም ፡
ይዞር ፡ ነበር ፤ በእነዚያም ፡ ስፍራዎች ፡ ሁሉ ፡
፲፯ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ይፈርድ ፡ ነበር ። ቤቱም ፡
በዚያ ፡ ነበረና ፡ ወደ ፡ አርማቴም ፡ ይመለስ ፡
ነበር ፤ በዚያም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ይፈርድ ፡
ነበር ፥ በዚያም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡
ሠራ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ሳሙኤል ፡ በሸመገለ ፡ ጊዜ ፡ ልጆቹን ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ፈራጆች ፡ አደረጋቸው ። ፪ የበኵር ፡ ልጁም ፡ ስም ፡ ኢዮኤል ÷ የሁለተኛውም ፡ ስም ፡ አብያ ፡ ነበረ ። እነርሱም ፡ በቤርሳቤህ ፡ ይፈርዱ ፡ ነበር ። ፫ ልጆቹም ፡ በመንገዱ ፡ አልሄዱም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ረብ ፡ ለማግኘት ፡ ፈቀቅ ፡ አሉ ÷ ጉቦም ፡ እየተቀበሉ ፡ ፍርድን ፡ ያጣምሙ ፡ ነበር ።

፬ የእስራኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሁሉ ፡ ተሰብስበው ፡ ወደ ፡ ሳሙኤል ፡ ወደ ፡ አርማቴም ፡ መጡና ፡— ፭ እነሆ ÷ አንተ ፡ ሸምግለሃል ÷ ልጆችህም ፡ በመንገድህ ፡ አይሄዱም ፤ አሁንም ፡ እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ የሚፈርድልን ፡ ንጉሥ ፡ አድርግልን ፡ አሉት ። ፮ የሚፈርድልንም ፡ ንጉሥ ፡ ስጠን ፡ ባሉት ፡ ጊዜ ፡ ነገሩ ፡ ሳሙኤልን ፡ አስከፋው ፤ ሳሙኤልም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸለየ ። ፯ እግዚአብሔርም ፡ ሳሙኤልን ፡ አለው ፡— በእነርሱ ፡ ላይ ፡ እንዳልነግሥ ፡ እኔን ፡ እንጂ ፡ አንተን ፡ አልናቁምና ፡ በሚሉህ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ የሕዝቡን ፡ ቃል ፡ ስማ ። ፰ ከግብጽ ፡ ከወጣኋቸው ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እኔን ፡ ትተው ፡ እንግዶች ፡ አማልክት ፡ በማምለካቸው ፡ እንደ ፡ ሠሩት ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ በአንተ ፡ ደግሞ ፡ ያደርጉብሃል ። ፱ አሁንም ፡ ቃላቸውን ፡ ስማ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ጽኑ ፡ ምስክር ፡ መስክርባቸው ÷ በእነርሱም ፡ ላይ ፡ የሚነግሠውን ፡ የንጉሡን ፡ ወግ ፡ ንገራቸው ።

፲ ሳሙኤልም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ፲፩ ንጉሥን ፡ ለፈለጉ ፡ ሕዝብ ፡ ነገራቸው ። እንዲህም ፡ አለ ፡— በእናንተ ፡ ላይ ፡ የሚነግሠው ፡ የንጉሡ ፡ ወግ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ወንዶች ፡ ልጆቻችሁን ፡ ወስዶ ፡ ሰረገለኞችና ፡ ፈረሰኞች ፡ ያደርጋቸዋል ÷ ፲፪ በሰረገሎቹም ፡ ፊት ፡ ይሮጣሉ ፤ ለራሱም ፡ የሻለቆችና ፡ የመቶ ፡ አለቆች ፡ ያደርጋቸዋል ፤ እርሻውንም ፡ የሚያርሱ ፡ እህሉንም ፡ የሚያጭዱ ፡ የጦር ፡ መሣሪያውንና ፡ የሰረገሎቹንም ፡ ዕቃ ፡ የሚሠሩ ፡ ይሆናሉ ። ፲፫ ሴቶች ፡ ልጆቻችሁንም ፡ ወስዶ ፡ ሽቶ ፡ ቀማሚዎችና ፡ ወጥቤቶች ፡ አበዛዎችም ፡ ያደርጋቸዋል ። ፲፬ ከእርሻችሁና ፡ ከወይናችሁም ፡ መልካም ፡ መልካሙን ፡ ወስዶ ፡ ለሎሌዎቹ ፡ ይሰጣቸዋል ። ፲፭ ከዘራችሁና ፡ ከወይናችሁም ፡ አሥራት ፡ ወስዶ ፡ ለጃንደረቦቹና ፡ ለሎሌዎቹ ፡ ይሰጣቸዋል ። ፲፮ ሎሌዎቻችሁንና ፡ ገረዶቻችሁን ÷ ከከብቶቻችሁና ፡ ከአህዮቻችሁም ፡ መልካም ፡ መልካሞቹን ፡ ወስዶ ፡ ያሠራቸዋል ። ፲፯ ከበጎቻችሁና ፡ ከፍየሎቻችሁ ፡ አሥራት ፡ ይወስዳል ፤ እናንተም ፡ ባሪያዎች ፡ ትሆኑታላችሁ ። ፲፰ በዚያም ፡ ቀን ፡ ለእናንተ ፡ ከመረጣችሁት ፡ ከንጉሣችሁ ፡ የተነሣ ፡ ትጮኻላችሁ ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ አልሰማችሁም ።

፲፱ ሕዝቡ ፡ ግን ፡ የሳሙኤልን ፡ ነገር ፡ ይሰማ ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ አለ ፡— እንዲህ ፡ አይሁን ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ንጉሥ ፡ ይሁንልን ÷ ፳ እኛም ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ እንሆናለን ፤ ንጉሣችንም ፡ ይፈርድልናል ÷ በፊታችንም ፡ ወጥቶ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ ይዋጋል ፡ አሉት ። ፳፩ ሳሙኤልም ፡ የሕዝቡን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ሰማ ÷ ለእግዚአብሔርም ፡ ተናገረ ። ፳፪ እግዚአብሔርም ፡ ሳሙኤልን ፡— ቃላቸውን ፡ ስማ ÷ ንጉሥም ፡ አንግሥላቸው ፡ አለው ። ሳሙኤልም ፡ የእስራኤልን ፡ ሰዎች ፡— እያንዳንዳችሁ ፡ ወደ ፡ ከተማችሁ ፡ ሂዱ ፡ አላቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ስሙ ፡ ቂስ ፡ የተባለ ፡ አንድ ፡ ብንያማዊ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ እርሱም ፡ የአቢኤል ፡ ልጅ ÷ የጽሮር ፡ ልጅ ÷ የብኮራት ፡ ልጅ ÷ የብንያማዊው ፡ የአፌቅ ፡ ልጅ ÷ ጽኑዕ ፡ ኀያል ፡ ሰው ፡ ነበረ ። ፪ ለእርሱም ፡ ሳኦል ፡ የሚባል ፡ የተመረጠ ፡ መልካም ፡ ልጅ ፡ ነበረው ፤ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከእርሱ ፡ ይልቅ ፡ መልካም ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ አልነበረም ፤ ከሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ከትከሻውና ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ቁመቱ ፡ ዘለግ ፡ ያለ ፡ ነበረ ። ፫ የሳኦልም ፡ አባት ፡ የቂስ ፡ አህዮች ፡ ጠፍተው ፡ ነበር ፤ ቂስም ፡ ልጁን ፡ ሳኦልን ፡— ከብላቴኖቹ ፡ አንዱን ፡ ወስደህ ፡ ተነሣ ÷ አህዮችንም ፡ ለመሻት ፡ ሂድ ፡ አለው ። ፬ በተራራማው ፡ በኤፍሬም ፡ አገርና ፡ በሻሊሻ ፡ አለፉ ÷ አላገኙአቸውምም ፤ በሻዕሊም ፡ ምድርም ፡ አለፉ ÷ በዚያም ፡ አልነበሩም ፤ በብንያም ፡ ምድርም ፡ አለፉ ÷ አላገኙአቸውምም ።

፭ ወደ ፡ ጹፍ ፡ ምድር ፡ በመጡ ፡ ጊዜም ፡ ሳኦል ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበረውን ፡ ብላቴና ፡— አባቴ ፡ ስለ ፡ አህዮች ፡ ማሰብ ፡ ትቶ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ እንዳይጨነቅ ÷ ና ÷ እንመለስ ፡ አለው ። ፮ እርሱም ፡— እነሆ ÷ አንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ በዚህች ፡ ከተማ ፡ አለ ፤ እርሱም ፡ የተከበረ ፡ ሰው ፡ ነው ÷ የሚናገረውም ፡ ሁሉ ፡ በእውነት ፡ ይፈጸማል ፤ አሁን ፡ ወደዚያ ፡ እንሂድ ፤ ምናልባት ፡ የምንሄድበትን ፡ መንገድ ፡ ይነግረናል ፡ አለው ። ፯ ሳኦልም ፡ ብላቴናውን ፡— እነሆ ÷ እንሄዳለን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ምን ፡ እናመጣለታለን ? እንጀራ ፡ ከከረጢታችን ፡ አልቆአልና ÷ እጅ ፡ መንሻም ፡ የለንምና ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ የምናመጣለት ፡ ምን ፡ አለን ? አለው ። ፰ ብላቴናውም ፡ ደግሞ ፡ ለሳኦል ፡ መለሰ ፡— እነሆ ÷ በእጄ ፡ የሰቅል ፡ ብር ፡ ሩቡ ፡ አለኝ ፤ እርሱንም ፡ መንገዳችንን ፡ እንዲነግረን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ እሰጣለሁ ፡ አለ ። ፱ ዛሬ ፡ ነቢይ ፡ የሚባለው ፡ ቀድሞ ፡ ባለ ፡ ራእይ ፡ ይባል ፡ ነበርና ፡ አስቀድሞ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ሰው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመጠየቅ ፡ ሲሄድ ፡— ኑ ÷ ወደ ፡ ባለ ፡ ራእይ ፡ እንሂድ ፡ ይል ፡ ነበር ። ፲ ሳኦልም ፡ ብላቴናውን ፡— የተናገርኸው ፡ ነገር ፡ መልካም ፡ ነው ፤ ና ÷ እንሂድ ፡ አለውና ፡ የእግ

ዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ወዳለበት ፡ ከተማ ፡ ሄዱ ። ፲፩ በከተማይቱም ፡ ዳገት ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፡ ቆነጃጅት ፡ ውኃውን ፡ ሊቀዱ ፡ ሲወጡ ፡ አገኙና ፡— ባለ ፡ ራእይ ፡ በዚህ ፡ አለ ፡ ወይ ? አሉአቸው ። ፲፪ እነርሱም ፡— አዎን ፤ እነሆ ፥ በፊታችሁ ፡ ነው ፤ ዛሬ ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ መጥቶአልና ፥ ዛሬም ፡ ሕዝቡ ፡ በኮረብታው ፡ ላይ ፡ ባለው ፡ መስገጃ ፡ መሥዋዕት ፡ ማቅረብ ፡ አለባቸውና ፡ ፈጥናችሁ ፡ ፲፫ ውጡ ። ወደ ፡ ከተማይቱም ፡ በገባችሁ ፡ ጊዜ ፡ መሥዋዕቱን ፡ እርሱ ፡ የሚባርክ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ እርሱ ፡ ሳይወጣ ፡ ሕዝቡ ፡ ምንም ፡ አይቀምሱምና ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የተጠሩት ፡ ይበላሉና ፡ ለመብላት ፡ ወደ ፡ ኮረብታው ፡ መስገጃ ፡ ሳይወጣ ፡ ታገኙታላችሁ ፤ በዚህም ፡ ጊዜ ፡ ታገኙ ፲፬ ታላችሁና ፡ አሁን ፡ ውጡ ፡ አሉአቸው ። ወደ ፡ ከተማይቱም ፡ ወጡ ፤ በከተማይቱም ፡ ውስጥ ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ እነሆ ፥ ሳሙኤል ፡ ወደ ፡ ኮረብታው ፡ መስገጃ ፡ ለመውጣት ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ መጣ ።

፲፭ ገናም ፡ ሳኦል ፡ ሳይመጣ ፡ ከአንድ ፡ ቀን ፡ በፊት ፡ እግዚአብሔር ፡ ሳሙኤልን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፲፮ ገልጦለት ፡ ነበር ፡— ነገ ፡ በዚህች ፡ ሰዓት ፡ ከብንያም ፡ አገር ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ እሰድድልሃለሁ ፤ ልቅሶአቸው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ የደረሰ ፡ ሕዝቤን ፡ ተመልክቻለሁና ፡ ለሕዝቤ ፡ ለእስራኤል ፡ አለቃ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ትቀባዋለህ ፥ ከፍልስጥኤማው ፲፯ ያንም ፡ እጅ ፡ ሕዝቤን ፡ ያድናል ። ሳሙኤልም ፡ ሳኦልን ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡— ያ ፡ የነገርሁህ ፡ ሰው ፡ እነሆ ፤ እርሱም ፡ በሕዝቤ ፡ ላይ ፡ ፲፰ ይሠለጥናል ፡ አለው ። ሳኦልም ፡ በበሩ ፡ ወደ ፡ ሳሙኤል ፡ ቀርቦ ፡— የባለ ፡ ራእዩ ፡ ቤት ፡ ወዴት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ እባክህ ፥ ንገረኝ ፡ አለው ። ፲፱ ሳሙኤልም ፡ መልሶ ፡ ሳኦልን ፡— ባለ ፡ ራእዩ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ ዛሬም ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ትበላላችሁና ፡ በፊቴ ፡ ወደ ፡ ኮረብታው ፡ መስገጃ ፡ ውጡ ፤ ነገም ፡ አሰናብትሃለሁ ፥ በልብህም ፡ ያለውን ፡ ፳ ሁሉ ፡ እነግርሃለሁ ፤ ከሦስት ፡ ቀንም ፡ በፊት ፡ የጠፉ ፡ አህዮችህ ፡ ተገኝተዋልና ፡ ልብህን ፡ አትጣልባቸው ። የእስራኤል ፡ ምኞት ፡ ለማን ፡ ነው ? ለአንተና ፡ ለአባትህ ፡ ቤት ፡ አይደለምን ? ፳፩ አለው ። ሳኦልም ፡ መልሶ ፡— እኔ ፡ ከእስራኤል ፡ ነገዶች ፡ ከሚያንስ ፡ ወገን ፡ የሆንሁ ፡ ብንያማዊ ፡ አይደለሁምን ? ወገኔስ ፡ ከብንያም ፡ ነገድ ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ የሚያንስ ፡ አይደለምን ? እንዲህስ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ ለምን ፡ ነገርኸኝ ? አለ ።

፳፪ ሳሙኤልም ፡ ሳኦልንና ፡ ብላቴናውን ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ አዳራሽ ፡ አገባቸው ፥ በመርፈቂያውም ፡ ራስ ፡ አስቀመጣቸው ፤ የተጠሩትም ፡ ሠላሳ ፡ ፳፫ ሰዎች ፡ ያህል ፡ ነበሩ ። ሳሙኤልም ፡ ወጥቤቱን ፡— በአንተ ፡ ዘንድ ፡ አኑረው ፡ ብዬ ፡ የሰጠሁህን ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ አምጣ ፡ አለው ። ፳፬ ወጥቤቱም ፡ ጭኑንና ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ የነበረውን ፡ አምጥቶ ፡ በሳኦል ፡ ፊት ፡ አኖረው ። ሳሙኤልም ፡— ሕዝቡን ፡ ከጠራሁ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ተወሰነው ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡ ለአንተ ፡ ተጠብቆአልና ፡ እነሆ ፥ የተቀመጠልህን ፡ በፊትህ ፡ አኑረህ ፡ ብላው ፡ አለ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ሳኦል ፡ ከሳሙኤል ፡ ጋር ፡ በላ ። ፳፭ ከኮረብታውም ፡ መስገጃ ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ ወረዱ ፤ ሳሙኤልም ፡ ለሳኦል ፡ በሰገነቱ ፡ ላይ ፡ መኝታ ፡ አዘጋጀለት ፥ ፳፮ እርሱም ፡ ተኛ ። ማልዶም ፡ ተነሡ ፤ በነጋም ፡ ጊዜ ፡ ሳሙኤል ፡ ሳኦልን ፡ ከሰገነቱ ፡ ላይ ፡ ጠርቶ ፡— ተነሣና ፡ ላሰናብትህ ፡ አለው ። ሳኦልም ፡ ተነሣ ፥ እርሱና ፡ ሳሙኤልም ፡ ሁለቱ ፡ ፳፯ ወደ ፡ ሜዳ ፡ ወጡ ። እነርሱም ፡ በከተማይቱ ፡ ዳር ፡ ሲወርዱ ፡ ሳሙኤል ፡ ሳኦልን ፡— ብላቴናውን ፡ ወደ ፡ ፊታችን ፡ እንዲያልፍ ፡ እዘዘው ፤ አንተ ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አሰማህ ፡ ዘንድ ፡ በዚህ ፡ ቁም ፡ አለው ። ብላቴናውም ፡ አለፈ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ ሳሙኤልም ፡ የዘይቱን ፡ ብርሌ ፡ ወስዶ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ አፈሰሰው ፥ ሳመውም ፥ እንዲህም ፡ አለው ፡— በርስቱ ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቀብቶሃል ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ሕዝብ ፡ ትገዛለህ ፥ በዙሪያውም ፡ ካሉ ፡ ፪ ጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡ ታድናቸዋለህ ። ዛሬ ፡ ከእኔ ፡ በተለየህ ፡ ጊዜ ፡ በብንያም ፡ ዳርቻ ፡ በጼልጻህ ፡ አገር ፡ ባለው ፡ በራሔል ፡ መቃብር ፡ አጠገብ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ታገኛለህ ፤ እነርሱም ፡— ልትሻቸው ፡ ሄደህ ፡ የነበርህላቸው ፡ አህዮች ፡ ተገኝተዋል ፤ እነሆም ፥ አባትህ ፡ ስለ ፡ አህዮች ፡ ማሰብ ፡ ትቶ ፡— የልጄን ፡ ነገር ፡ እንዴት ፡ አደርጋለሁ ? እያለ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ይጨነቃል ፡ ፫ ይሉሃል ። ከዚያም ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ትሄዳለህ ፤ ወደ ፡ ታቦር ፡ ወደ ፡ ትልቁ ፡ ዛፍ ፡ ትደርሳለህ ፥ በዚያም ፡ ሦስት ፡ ሰዎች ፥ አንዱ ፡ ሦስት ፡ የፍየል ፡ ጠቦቶች ፥ ሁለተኛው ፡ ሦስት ፡ ዳቦ ፥ ሦስተኛውም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ አቁማዳ ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ቤቴል ፡ ፬ ሲወጡ ፡ ያገኙሃል ፤ ሰላምታም ፡ ይሰጡሃል ፥ ሁለትም ፡ ዳቦ ፡ ይሰጡሃል ፥ ከእጃቸውም ፡ ትቀ ፭ በላለህ ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የፍልስጥኤማውያን ፡ ጭፍራ ፡ ወዳለበት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኮረብታ ፡ ትመጣለህ ፤ ወደዚያም ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ በደረስህ ፡ ጊዜ ፥ በገናና ፡ ከበሮ ፡ እምቢልታና ፡ መሰንቆ ፡ ይዘው ፡ ትንቢት ፡ እየተናገሩ ፡ ከኮረብታው ፡ መስገጃ ፡ የሚወርዱ ፡ የነቢያት ፡ ፮ ጉባኤ ፡ ያገኙሃል ። የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በኃይል ፡ ይወርድብሃል ፥ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ትንቢት ፡ ትናገራለህ ፥ እንደ ፡ ሌላ ፡ ሰውም ፡ ፯ ሆነህ ፡ ትለወጣለህ ። እነዚህም ፡ ምልክቶች ፡ በደረሱህ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነውና ፡ እጅህ ፡ የምታገኘውን ፡ ሁሉ ፡ አድርግ ። ፰ በፊቴም ፡ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ ትወርዳለህ ፤ እኔም ፥ እነሆ ፥ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ አቀርብ ፡ ዘንድ ፥ የደኅንነትንም ፡ መሥዋዕት ፡ እሠዋ ፡

ዘንድ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እወርዳለሁ ፤ እኔ ፡ ወደ ፡
አንተ ፡ እስክመጣና ፡ የምታደርገውን ፡ እስክነ
ግርህ ፡ ድረስ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ትቆያለህ ።
፱ ፡ ከሳሙኤልም ፡ ዘንድ ፡ ለመሄድ ፡ ፊቱን ፡
በመለሰ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሌላ ፡ ልብ ፡ ለወ
ጠለት ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ እነዚህ ፡ ምልክቶች ፡
፲ ፡ ሁሉ ፡ ደረሱለት ። ወደዚያም ፡ ከረብታ ፡ በደ
ረሰ ፡ ጊዜ ÷ እነሆ ÷ የነቢያት ፡ ጉባኤ ፡ አገኙት ፤
የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በኃይል ፡ ወረደ
በት ÷ በመካከላቸውም ፡ ትንቢት ፡ ተናገረ ።
፲፩ ፡ ቀድሞም ፡ የሚያውቁት ፡ ሁሉ ፡ ከነቢያት ፡
ጋር ፡ ትንቢት ፡ ሲናገር ፡ በዩት ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡ ፡
እርስ ፡ በርሳቸው ፡— የቂስን ፡ ልጅ ፡ ያገኘው ፡
ምንድር ፡ ነው ? በውኑ ፡ ሳኦል ፡ ከነቢያት ፡
፲፪ ፡ ወገን ፡ ነውን ? ተባባሉ ። ከዚያም ፡ ስፍራ ፡
ያለ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡— አባታቸውስ ፡ ማን ፡ ነው ?
ብሎ ፡ መለሰ ። ስለዚህም ፡— ሳኦል ፡ ደግሞ ፡
ከነቢያት ፡ ወገን ፡ ነውን ? የሚል ፡ ምሳሌ ፡ ሆነ ።
፲፫ ፡ ትንቢት ፡ መናገሩንም ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡
ከረብታው ፡ መስገጃ ፡ መጣ ።
፲፬ ፡ አጎቱም ፡ ሳኦልንና ፡ ብላቴናውን ፡— ወዴት ፡
ሄዳችሁ ፡ ኖሮአል ? አላቸው ። እርሱም ፡— አህ
ዮችን ፡ ልንሻ ፡ ሄደን ፡ ነበር ፤ ባጣናቸውም ፡
፲፭ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሳሙኤል ፡ መጣን ፡ አለ ። የሳኦ
ልም ፡ አጎት ፡— ሳሙኤል ፡ የነገረህን ÷ እባክህ ÷
፲፮ ፡ ንገረኝ ፡ አለው ። ሳኦልም ፡ አጎቱን ፡— አህ
ዮች ፡ እንደ ፡ ተገኙ ፡ ገለጠልን ፡ አለው ፤ ነገር ፡
ግን ፡ ሳሙኤል ፡ የነገረውን ፡ የመንግሥትን ፡
ነገር ፡ አላወራለትም ።
፲፯ ፡ ሳሙኤልም ፡ ሕዝቡን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
፲፰ ፡ ወደ ፡ ምጽጳ ፡ ጠራ ። የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡—
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እስራኤልን ፡ ከግብጽ ፡ አወጣሁ ÷
ከግብጻውያንም ፡ እጅ ፡ ከሚያስጨንቁአችሁም ፡
፲፱ ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ አዳንኋችሁ ። ዛሬ ፡
ግን ፡ ከመከራችሁና ፡ ከጭንቃችሁ ፡ ሁሉ ፡ ያዳ
ናችሁን ፡ አምላካችሁን ፡ ንቃችሁ ፡— እንዲህ ፡
አይሁን ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ንጉሥ ፡ አንግሥልን ፡
አላችሁት ። አሁንም ፡ በየነገዳችሁና ፡ በየወገና
ችሁ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቅረቡ ፡ አላ
፳ ፡ ቸው ። ሳሙኤልም ፡ የእስራኤልን ፡ ነገዶች ፡
ሁሉ ፡ አቀረበ ÷ ዕጣውም ፡ በብንያም ፡ ነገድ ፡
፳፩ ፡ ላይ ፡ ወደቀ ። የብንያምንም ፡ ነገድ ፡ በየወገና
ቸው ፡ አቀረበ ÷ ዕጣውም ፡ በማጥሪ ፡ ወገን ፡
ላይ ፡ ወደቀ ። የማጥሪንም ፡ ወገን ፡ በየሰዉ ፡
አቀረበ ÷ ዕጣውም ፡ በቂስ ፡ ልጅ ፡ በሳኦል ፡ ላይ ፡
፳፪ ፡ ወደቀ ፤ ፈለጉትም ÷ አላገኙትምም ። ከእግዚ
አብሔርም ፡— ገና ፡ ወደዚህ ፡ የሚመጣ ፡ ሰው ፡
አለን ? ብለው ፡ ደግሞ ፡ ጠየቁት ፤ እግዚአብ
ሔርም ፡— እነሆ ÷ በዕቃ ፡ መካከል ፡ ተሸሽጎአል ፡
፳፫ ፡ ብሎ ፡ መለሰ ። እነርሱም ፡ ሮጠው ፡ ከዚያ ፡
አመጡት ፤ እርሱም ፡ በሕዝቡ ፡ መካከል ፡ ቆመ ÷
ከሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ከትከሻው ፡ ወደ ፡
፳፬ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ቁመተ ፡ ረጅም ፡ ነበረ ። ሳሙ
ኤልም ፡ ለሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡— ከሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡
እርሱን ፡ የሚመስል ፡ እንደሌለ ፡ እግዚአብሔር ፡
የመረጠውን ፡ ታያላችሁን ? አላቸው ፤ ሕዝ
ቡም ፡ ሁሉ ፡— ንጉሥ ፡ ሕያው ፡ ይሁን ፡ እያሉ ፡
እልልታ ፡ አደረጉ ።
፳፭ ፡ ሳሙኤልም ፡ የመንግሥቱን ፡ ወግ ፡ ነገረ ÷
በመጽሐፍም ፡ ጻፈው ፡ በእግዚአብሔርም ፡
ፊት ፡ አኖረው ። ሳሙኤልም ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡
፳፮ ፡ ወደ ፡ እየቤታቸው ፡ አሰናበታቸው ። ሳኦልም ፡
ወደ ፡ ቤቱ ፡ ወደ ፡ ጊብዓ ፡ ሄደ ፤ እግዚአብ
ሔር ፡ ልባቸውን ፡ የነካ ፡ ኃያላንም ፡ ከእርሱ ፡
፳፯ ፡ ጋር ፡ ሄዱ ። ምናምንቴዎች ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡—
ይህ ፡ ሰው ፡ እንዴት ፡ ያድነናል ? ብለው ፡
ናቁት ÷ እጅ ፡ መንሻም ፡ አላመጡለትም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ፡ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ከአንድ ፡ ወር ፡ በኋላ ፡ አሞ
ናዊው ፡ ናዖስ ፡ ወጣ ÷ በኢያቢስ ፡ ገለዓድም ፡
ሰፈረ ፤ የኢያቢስም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡— ቃል ፡
ኪዳን ፡ አድርግልን ÷ እኛም ፡ እንገዛልሃለን ፡
፪ ፡ አሉት ። አሞናዊውም ፡ ናዖስ ፡— ቀኝ ፡ ዓይናች
ሁን ፡ ሁሉ ፡ በማውጣት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደር
ግላችኋለሁ ፤ በእስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ስድብ ፡
፫ ፡ አደርጋለሁ ፡ አላቸው ። የኢያቢስም ፡ ሽማግ
ሌዎች ፡— ወደ ፡ እስራኤል ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ መል
ክተኞችን ፡ እንድንልክ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ቆይልን ፤
ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የሚያድነን ፡ ባይኖር ፡ ወደ ፡
፬ ፡ አንተ ፡ እንመጣለን ፡ አሉት ። መልክተኞቹም ፡
ሳኦል ፡ ወዳለበት ፡ ወደ ፡ ጊብዓ ፡ መጥተው ፡
ይህን ፡ ነገር ፡ በሕዝቡ ፡ ጆሮ ፡ ተናገሩ ፤ ሕዝ
ቡም ፡ ሁሉ ፡ ድምፃቸውን ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡
፭ ፡ አለቀሱ ። እነሆም ÷ ሳኦል ፡ በሬዎቹን ፡ ተከ
ትሎ ፡ ከእርሻው ፡ መጣ ፤ ሳኦልም ፡— ሕዝቡ ፡
የሚያለቅስ ፡ ምን ፡ ሆኖ ፡ ነው ? አለ ። የኢያቢ
ስንም ፡ ሰዎች ፡ ነገር ፡ ነገሩት ።
፮ ፡ ይህንም ፡ ነገር ፡ በሰማው ፡ ጊዜ ፡ በሳኦል ፡ ላይ ፡
የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ በኃይል ፡ ወረደ ÷
፯ ፡ ቍጣውም ፡ እጅግ ፡ ነደደ ። ጥምዱንም ፡ በሬ
ዎች ፡ ወስዶ ፡ ቈራረጣቸው ÷ ወደ ፡ እስራኤ
ልም ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ በመልክተኞቹ ፡ እጅ ፡
ሰደደና ፡— ሳኦልንና ፡ ሳሙኤልን ፡ ተከትሎ ፡
የማይወጣ ፡ ሁሉ ÷ በበሬዎቹ ፡ እንዲሁ ፡ ይደ
ረግ ፡ አለ ። ድንጋጤም ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ከእ
ግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወደቀ ÷ እንደ ፡ አንድ ፡
፰ ፡ ሰውም ፡ ሆነው ፡ ወጡ ። በቤዜቅም ፡ ቈጠራ
ቸው ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡
ሺህ ÷ የይሁዳም ፡ ሰዎች ፡ ሠላሳ ፡ ሺህ ፡ ነበሩ ።
፱ ፡ የመጡትንም ፡ መልክተኞች ፡— የኢያቢስ ፡
ገለዓድን ፡ ሰዎች ፡— ነገ ፡ ፀሐይ ፡ በተኰሰ ፡
ጊዜ ፡ ማዳን ፡ ይሆንላችኋል ፡ በሉአቸው ፡ አሉ
አቸው ። መልክተኞችም ፡ መጥተው ፡ ለኢያ
፲ ፡ ቢስ ፡ ሰዎች ፡ ነገሩ ፤ ደስም ፡ አላቸው ። የኢ
ያቢስም ፡ ሰዎች ፡— ነገ ፡ እንወጣላችኋለን ÷
ደስ ፡ የሚያሰኛችሁንም ፡ አድርጉብን ፡ አሉ ።

፲፩፡ በነጋውም ፡ ሳኦል ፡ ሕዝቡን ፡ በሦስት ፡ ወገን ፡ አደረጋቸው ፤ ወገግም ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ መካከል ፡ ገቡ ፥ ቀትርም ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡ አሞናውያንን ፡ መቱ ፤ የቀሩትም ፡ ተበ ተኑ ፥ ሁለትም ፡ በአንድ ፡ ላይ ፡ ሆነው ፡ አልቀ ሩላቸውም ።

፲፪፡ ሕዝቡም ፡ ሳሙኤልን ፦ ሳኦል ፡ አይንገሥ ብን ፡ ያሉ ፡ እነማናቸው ? አውጡአቸውና ፡ እንግደላቸው ፡ አሉት ። ፲፫፡ ሳኦልም ፦ ዛሬ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ ለእስራኤል ፡ ማዳን ፡ አድርጎአልና ፡ ዛሬ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ አይሞትም ፡ አለ ።

፲፬፡ ሳሙኤልም ፡ ሕዝቡን ፦ ኑ ፥ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ እንሂድ ፥ በዚያም ፡ መንግሥቱን ፡ እናድስ ፡ ፲፭፡ አላቸው ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ ሄዱ ፥ በዚያም ፡ ሳኦልን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በጌ ልገላ ፡ አነገሡት ፤ በዚያም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረቡ ፤ በዚ ያም ፡ ሳኦልና ፡ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ታላቅ ፡ ደስታ ፡ አደረጉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩፡ ሳሙኤልም ፡ እስራኤልን ፡ ሁሉ ፡ አለ ፦ የነገራችሁኝን ፡ ሁሉ ፡ ሰምቼ ፡ አንግሼላችኋ ፪፡ ለሁ ። አሁንም ፥ እነሆ ፥ ንጉሡ ፡ በፊታችሁ ፡ ይሄዳል ፤ እኔም ፡ አርጅቻለሁ ፡ ሸምግያለሁም ፤ እነሆም ፥ ልጆቼ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ናቸው ፤ እኔም ፡ ከሕፃንነቴ ፡ ጀምሬ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ፫፡ በፊታችሁ ፡ ሄድሁ ። እነሆኝ ፤ በእግዚአብሔ ርና ፡ እርሱ ፡ በቀባው ፡ ፊት ፡ መስክሩብኝ ፤ የማንን ፡ በሬ ፡ ወሰድሁ ? የማንንስ ፡ አህያ ፡ ወሰድሁ ? ማንንስ ፡ ሸነገልሁ ? በማንስ ፡ ላይ ፡ ግፍ ፡ አደረግሁ ? ዓይኖቼንስ ፡ ለማሳወር ፡ ከማን ፡ እጅ ፡ጉቦ ፡ ተቀበልሁ ? እኔም ፡ እመል ፬፡ ስላችኋለሁ ። እነርሱም ፦ አልሸነገልኸንም ፥ ግፍም ፡ አላደረግህብንም ፥ ከሰውም ፡ እጅ ፡ ፭፡ ምንም ፡ አልወሰድህም ፡ አሉ ። እርሱም ፦ በእጄ ፡ ምንም ፡ እንዳላገኛችሁ ፡ እግዚአብሔ ርና ፡ እርሱ ፡ የቀባው ፡ ዛሬ ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ምስክሮች ፡ ናቸው ፡ አላቸው ፤ እነርሱም ፦ ምስክር ፡ ነው ፡ አሉ ።

፮፡ ሳሙኤልም ፡ ሕዝቡን ፡ አለ ፦ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ ያላቀ ፥ አባቶቻችሁንም ፡ ከግብጽ ፡ ፯፡ ምድር ፡ ያወጣ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ። አሁ ንም ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእናንተና ፡ ለአባቶቻ ችሁ ፡ ስላደረገው ፡ ጽድቅ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብ ሔር ፡ ፊት ፡ እምዋገታችሁ ፡ ዘንድ ፡ በዚህ ፡ ፰፡ ቁሙ ። ያዕቆብና ፡ ልጆቹ ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ ግብጻውያን ፡ አስጨነቁአቸው ፤ አባቶቻችሁም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ፥ እግዚአብሔርም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ ላከ ፥ አባቶቻችሁንም ፡ ከግብጽ ፡ አውጥተው ፡ በዚህ ፡ ፱፡ ቦታ ፡ አኖሩአቸው ። አምላካቸውንም ፡ እግዚ አብሔርን ፡ ረሱ ፥ ለአሶር ፡ ሠራዊትም ፡ አለቃ ፡ ለሲሣራ ፡ እጅ ፥ ለፍልስጥኤማውያንም ፡ እጅ ፥ ለሞዓብም ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፥ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ተዋጉ ። ፲፡ እነርሱም ፦ እግ ዚአብሔርን ፡ ትተን ፡ በአሊምንና ፡ አስታሮ ትን ፡ በማምለካችን ፡ በድለናል ፤ አሁንም ፡ ከጠ ላቶቻችን ፡ እጅ ፡ አድነን ፥ እናመልክህማለን ፡ ፲፩፡ ብለው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ። እግዚ አብሔርም ፡ ይሩበአልን ፥ ባርቅንም ፥ ዮፍታ ሔንም ፥ ሳሙኤልንም ፡ ላከ ፥ በዙሪያችሁም ፡ ካሉት ፡ ከጠላቶቻችሁ ፡ እጅ ፡ አዳናችሁ ፤ ተዘል ፲፪፡ ላችሁም ፡ ተቀመጣችሁ ። የአሞንም ፡ ልጆች ፡ ንጉሥ ፡ ናያስ ፡ እንደ ፡ መጣባችሁ ፡ በያችሁ ፡ ጊዜ ፥ አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ንጉሣችሁ ፡ ሳለ ፦ እንዲህ ፡ አይሁን ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ንጉሥ ፡ ፲፫፡ ይንገሥልን ፡ አላችሁኝ ። አሁንም ፡ የመረጣ ችሁትንና ፡ የፈለጋችሁትን ፡ ንጉሥ ፡ እዩ ፤ እነ ሆም ፥ እግዚአብሔር ፡ ንጉሥ ፡ አደረገላችሁ ። ፲፬፡ እግዚአብሔርን ፡ ብትፈሩ ፡ ብታመልኩትም ፥ ቃሉንም ፡ ብትሰሙ ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ትእ ዛዝ ፡ ላይ ፡ ባታምፁ ፥ እናንተና ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ የነገሠው ፡ ንጉሥ ፡ አምላካችሁን ፡ እግዚ አብሔርን ፡ ብትከተሉ ፥ መልካም ፡ ይሆንላች ፲፭፡ ኋል ። ነገር ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ባትሰሙ ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ትእዛዝ ፡ ላይ ፡ ብታምፁ ፥ በእናንተና ፡ በንጉሣችሁ ፡ ላይ ፡ ፲፮፡ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ትሆናለች ። አሁንም ፡ ቁሙ ፥ እግዚአብሔርም ፡ በዓይናችሁ ፡ ፊት ፡ ወደሚያደርገው ፡ ወደዚህ ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡ ተመ ፲፯፡ ልከቱ ። የስንዴ ፡ መከር ፡ ዛሬ ፡ አይደለምን ? ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እጮኻለሁ ፥ እርሱም ፡ ነጐድጓድና ፡ ዝናብ ፡ ይልካል ፤ እናንተም ፡ ንጉሥ ፡ በመለመናችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያደረጋችሁት ፡ ክፋት ፡ ታላቅ ፡ እንደ ፡ ፲፰፡ ሆነ ፡ ታውቃላችሁ ፡ ታያላችሁም ። ሳሙኤ ልም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኸ ፥ እግዚአ ብሔርም ፡ በዚያን ፡ ቀን ፡ ነጐድጓድና ፡ ዝናብ ፡ ላከ ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርንና ፡ ሳሙኤልን ፡ እጅግ ፡ ፈሩአቸው ።

፲፱፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ሳሙኤልን ፦ ንጉሥ ፡ በመ ለመናችን ፡ በኃጢአታችን ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ይህን ፡ ክፋት ፡ ጨምረናልና ፡ እንዳንሞት ፡ ስለ ፡ ባሪ ያዎችህ ፡ ወደ ፡ አምላክህ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፳፡ ጸልይ ፡ አሉት ። ሳሙኤልም ፡ ሕዝቡን ፡ አለ ፦ አትፍሩ ፤ በእውነት ፡ ይህን ፡ ክፋት ፡ ሁሉ ፡ አደረጋችሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ በፍ ጹም ፡ ልባችሁ ፡ አምልኩት ፡ እንጂ ፡ እግዚአ ፳፩፡ ብሔርን ፡ ከመከተል ፡ ፈቀቅ ፡ አትበሉ ። ምና ምንቴ ፡ ነውና ፡ የማይረባንና ፡ የማያድን ፡ ከን ፳፪፡ ቱን ፡ ነገር ፡ ለመከተል ፡ ፈቀቅ ፡ አትበሉ ። እግ ዚአብሔር ፡ ለእርሱ ፡ ሕዝብ ፡ ያደርጋችሁ ፡ ዘንድ ፡ ወድዶአልና ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ፳፫፡ ታላቅ ፡ ስሙ ፡ ሕዝቡን ፡ አይተውም ። ደግሞ ፡ መልካሙንና ፡ ቅኑን ፡ መንገድ ፡ አስተምራች ኋለሁ ፡ እንጂ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ መጸለይን ፡ በመ ተው ፡ እግዚአብሔርን ፡ እበድል ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡

፳፬ ከእኔ ፡ ይራቅ ፡፡ ብቻ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፍሩ ፥ ያደረገላችሁንም ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡ አይታችኋልና ፡ በፍጹም ፡ ልባችሁ ፡ በእውነት ፡ አምልኩት ፡፡ ፳፭ ነገር ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ ብትሠሩ ፡ እናንተም ፡ ንጉሣችሁም ፡ ትጠፋላችሁ ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ፡፡

፩ ሳኦልም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ፪ ከነገሠ ፡ በኋላ ፥ ሳኦል ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ከእስራኤል ፡ መረጠ ፤ ሁለቱም ፡ ሺህ ፡ በማክማስና ፡ በቤቴል ፡ ተራራ ፡ ከሳኦል ፡ ጋር ፡ ነበሩ ፥ አንዱም ፡ ሺህ ፡ በብንያም ፡ ጊብዓ ፡ ከዮናታን ፡ ጋር ፡ ነበሩ ፤ የቀረውንም ፡ ሕዝብ ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ድንኳኑ ፡ አሰናበተ ፡፡ ፫ ዮናታንም ፡ በናሲብ ፡ ውስጥ ፡ የነበረውን ፡ የፍልስጥኤማውያንን ፡ ጭፍራ ፡ መታ ፥ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ያን ፡ ሰሙ ፤ ሳኦልም ፡— ዕብራውያን ፡ ይስሙ ፡ ብሎ ፡ በአገሩ ፡ ሁሉ ፡ ቀንደ ፡ መለከት ፡ ነፋ ፡፡ ፬ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ሳኦል ፡ የፍልስጥኤማውያንን ፡ ጭፍራ ፡ እንደ ፡ መታ ፥ ደግሞም ፡ እስራኤል ፡ በፍልስጥኤማውያን ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተጸየፉ ፡ ሰሙ ፤ ሕዝቡም ፡ ሳኦልን ፡ ለመከተል ፡ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ ተሰበሰቡ ፡፡

፭ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ከእስራኤል ፡ ጋር ፡ ለመዋጋት ፡ ተሰበሰቡ ፤ ሠላሳ ፡ ሺህ ፡ ሰረገሎች ፡ ስድስትም ፡ ሺህ ፡ ፈረሰኞች ፡ በባሕርም ፡ ዳር ፡ እንዳለ ፡ አሸዋ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ነበሩ ፤ ወጥተውም ፡ ከቤትአዌን ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ በማክማስ ፡ ሰፈሩ ፡፡ ፮ ሕዝቡም ፡ ተጨንቀው ፡ ነበርና ፡ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ በጭንቀት ፡ እንዳሉ ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡ ፡ በዋሻና ፡ በእሾህ ፡ ቍጥቋጦ ፡ በገደልና ፡ በግንብ ፡ በጕድጓድም ፡ ውስጥ ፡ ተሸሸጉ ፡፡ ፯ ከዕብራውያንም ፡ ዮርዳኖስን ፡ ተሻግረው ፡ ወደ ፡ ጋድና ፡ ወደ ፡ ገለዓድ ፡ ምድር ፡ ሄዱ ፤ ሳኦል ፡ ግን ፡ ገና ፡ በጌልገላ ፡ ነበረ ፥ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ተንቀጥቅጠው ፡ ተከተሉት ፡፡ ፰ ሳኦልም ፡ ሳሙኤል ፡ እንደ ፡ ቀጠረው ፡ ጊዜ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ቆየ ፤ ሳሙኤል ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ አልመጣም ፥ ሕዝቡም ፡ ከእርሱ ፡ ተለይተው ፡ ተበታተኑ ፡፡ ፱ ሳኦልም ፡— የሚቃጠል ፡ መሥዋዕትና ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ አምጡልኝ ፡ አለ ፡፡ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ ፲ አሳረገ ፡፡ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ ማሳረግ ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፥ እነሆ ፥ ሳሙኤል ፡ መጣ ፤ ሳኦልም ፡ እንዲመርቀው ፡ ሊገናኘው ፡ ፲፩ ወጣ ፡፡ ሳሙኤልም ፡— ያደረግኸው ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለ ፡፡ ሳኦልም ፡— ሕዝቡ ፡ ከእኔ ፡ ተለይተው ፡ እንደ ፡ ተበታተኑ ፥ አንተም ፡ በቀጠርው ፡ እንዳልመጣህ ፥ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ወደ ፡ ማክማስ ፡ እንደ ፡ ተሰበሰቡ ፡ አየሁ ፤ ፲፪ ስለዚህ ፡— ፍልስጥኤማውያን ፡ አሁን ፡ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ ይወርዱብኛል ፥ እኔም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሞገስ ፡ አልለመንሁም ፡ አልሁ ፤ ስለዚህም ፡ ሳልታገሥ ፡ የሚቃጠልን ፡ መሥዋዕት ፡ አሳረግሁ ፡ አለ ፡፡ ፲፫ ሳሙኤልም ፡ ሳኦልን ፡— አላበጀህም ፤ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያዘዘህን ፡ ትእዛዝ ፡ አልጠበቅህም ፤ ዛሬ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥትህን ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ለዘላለም ፡ አጽንቶልህ ፡ ነበር ፡፡ ፲፬ አሁንም ፡ መንግሥትህ ፡ አይጸናም ፤ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ልቡ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ መርጦአል ፤ እግዚአብሔርም ፡ ያዘዘህን ፡ አልጠበቅህምና ፡ እግዚአብሔር ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ አዝዞታል ፡ አለው ፡፡

፲፭ ሳሙኤልም ፡ ከጌልገላ ፡ ተነሥቶ ፡ መንገዱን ፡ ሄደ ፤ የቀሩትም ፡ ሕዝብ ፡ ሳኦልን ፡ ተከትለው ፡ ሰልፈኞቹን ፡ ሊገናኙ ፡ ሄዱ ፡፡ ከጌልገላም ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ ብንያም ፡ ጊብዓ ፡ መጡ ፤ ሳኦልም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩትን ፡ ሕዝብ ፡ ቈጠረ ፥ ስድስት ፡ መቶም ፡ የሚያህሉ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፡፡ ፲፮ ሳኦልና ፡ ልጁ ፡ ዮናታንም ፡ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩ ፡ ሕዝብ ፡ በብንያም ፡ ጊብዓ ፡ ተቀመጡ ፤ ፍልስጥኤማውያንም ፡ በማክማስ ፡ ሰፈሩ ፡፡ ፲፯ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ ሰፈር ፡ ማራኪዎች ፡ በሦስት ፡ ክፍል ፡ ሆነው ፡ ወጡ ፤ አንዱም ፡ ክፍል ፡ በዖፍራ ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡ ሦጋል ፡ ምድር ፡ ሄደ ፡፡ ፲፰ ሁለተኛው ፡ ክፍል ፡ ወደ ፡ ቤትሖሮን ፡ መንገድ ፡ ዞረ ፤ ሦስተኛውም ፡ ክፍል ፡ በበረሀው ፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡ ወደ ፡ ስቦይም ፡ ሸለቆ ፡ በሚመለከተው ፡ በዳርቻ ፡ መንገድ ፡ ዞረ ፡፡

፲፱ ፍልስጥኤማውያንም ፡— ዕብራውያን ፡ ሰይፍና ፡ ጦር ፡ እንዳይሠሩ ፡ ብለው ፡ ነበርና ፡ በእስራኤል ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ብረት ፡ ሠሪ ፡ አልተገኘም ፡፡ ፳ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ የማረሻውን ፡ ጫፍና ፡ ማጭዱን ፡ መጥረቢያውንና ፡ መቆፈሪያውን ፡ ይስል ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ይወርድ ፡ ነበር ፡፡ ፳፩ ለማረሻው ፡ ጫፍና ፡ ለመቆፈሪያው ፡ ዋጋው ፡ የሰቅል ፡ ከ፫ ፡ እጅ ፡ ፪ቱ ፡ እጅ ፡ ነበረ ፡፡ መጥረቢያውንም ፡ ለማሳል ፡ መውጊያውንም ፡ ለማበጀት ፡ ዋጋው ፡ የሰቅል ፡ ከ፫ ፡ እጅ ፡ ፩ዱ ፡ እጅ ፡ ነበረ ፡፡ ፳፪ ስለዚህም ፡ በሰልፍ ፡ ቀን ፡ ሰይፍና ፡ ጦር ፡ ከሳኦልና ፡ ከዮናታን ፡ ጋር ፡ በነበሩ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ አልተገኘም ፤ ብቻ ፡ በሳኦልና ፡ በልጁ ፡ በዮናታን ፡ ዘንድ ፡ ተገኘ ፡፡ ፳፫ የፍልስጥኤማውያንም ፡ ጭፍራ ፡ ወደ ፡ ማክማስ ፡ መተላለፊያ ፡ ወጡ ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ፡፡

፩ አንድ ፡ ቀንም ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ የሳኦል ፡ ልጅ ፡ ዮናታን ፡ ጋሻ ፡ ጃግሬውን ፡— ና ፥ በዚያ ፡ በኩል ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ጭፍራ ፡ እንለፍ ፡ አለው ፤ ለአባቱም ፡ አልነገረውም ፡፡ ፪ ሳኦልም ፡ በመጌዶን ፡ ባለው ፡ በሮማኑ ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ በጊብዓ ፡ ዳርቻ ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ፤ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበረው ፡ ሕዝብ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ የሚያህል ፡ ሰው ፡ ነበረ ፡፡ ፫ የኢካቦድ ፡ ወንድም ፡ የአኪጠብ ፡ ልጅ ፡ የፊንሐስ ፡ ልጅ ፡ የዔሊ ፡ ልጅ ፡ በሴሎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ካህን ፡ የሆነ ፡

ኤፉድም፡የለበስ፡አኪያ፡አብሮ፡ነበር፤ሕዝቡ፡
፬፤ ዮናታን፡እንደ፡ሄደ፡አላወቁም ። ዮናታንም፡
ወደ፡ፍልስጥኤማውያን፡ጭፍራ፡ሊሻገርበት፡
በወደደው ፡ መተላለፊያ ፡ መካከል ፡ በወዲህ ፡
አንድ፡ሾጣጣ፡በወዲህ፡አንድ፡ሾጣጣ፡ድን
ጋዮች፡ነበሩ ፤ የአንዱም ፡ ስም ፡ ቦጼጽ ፡ የሁ
፭፤ ለተኛውም ፡ ስም ፡ ሴኔ ፡ ነበረ ። አንዱም ፡
ሾጣጣ፡በማክማስ፡አንጻር፡በሰሜን፡በኩል ፥
ሁለተኛውም ፡ በጊብዓ ፡ አንጻር ፡ በደቡብ ፡
በኩል ፡ የቆመ ፡ ነበሩ ።
፮፤ ዮናታንም፡ጋሻ፡ጃግሬውን፡— ና ፥ ወደ፡እነ
ዚህ፡ቈላፉን፡ጭፍራ፡እንለፍ፤በብዙ ፡ ወይም፡
በጥቂት ፡ ማዳን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አያስቸግረ
ውምና፡ምናልባት፡እግዚአብሔር፡ይሠራልን፡
፯፤ ይሆናል፡አለው ። ጋሻ፡ጃግሬውም ፡— ልብህ፡
ያሰኘህን፡ሁሉ፡አድርግ፤እነሆ፥ከአንተ፡ጋር፡
ነኝ ፤ እንደ ፡ አንተ ፡ ልብ ፡ ሁሉ ፡ የእኔም ፡ ልብ፡
፰፤ እንዲሁ ፡ ነው ፡ አለው ። ዮናታንም ፡ አለ ፡—
እነሆ ፥ ወደ ፡ ሰዎቹ ፡ እናልፋለን ፡ እንገለጥላቸ
፱፤ ውማለን ፤ እነርሱም ፡— ወደ ፡ እናንተ ፡ እስ
ክንመጣ ፡ ድረስ ፡ ቆዩ ፡ ቢሉን ፡ በስፍራችን ፡
እንቆማለን ፥ ወደ ፡ እነርሱም ፡ አንወጣም ።
፲፤ ነገር ፡ ግን ፡— ወደ ፡ እኛ ፡ ውጡ ፡ ቢሉን ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ በእጃችን ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶአቸዋ
ልና ፡ እንወጣለን ፤ ምልክታችንም ፡ ይህ ፡ ይሆ
፲፩፤ ናል ። ሁለታቸውም ፡ ለፍልስጥኤማውያን ፡
ጭፍራ ፡ ተገለጡ ፤ ፍልስጥኤማውያንም ፡—
እነሆ ፥ ዕብራውያን ፡ ከተሸሸጉበት ፡ ጕድጓድ ፡
፲፪፤ ይወጣሉ ፡ አሉ ። የጭፍራው ፡ ሰዎችም ፡ ዮና
ታንንና፡ጋሻ፡ጃግሬውን፡— ወደ፡እኛ፡ውጡ፥
አንድ ፡ ነገርም ፡ እናሳያችኋለን ፡ አሉ ። ዮናታ
ንም ፡ ጋሻ ፡ ጃግሬውን ፡— እግዚአብሔር ፡ በእ
ስራኤል ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶአቸዋልና ፡ ተከ
፲፫፤ ተለኝ ፡ አለው ። ዮናታንም ፡ በእጁና ፡ በእ
ግሩ ፡ ወጣ ፥ ጋሻ ፡ ጃግሬውም ፡ ተከተለው ፤ ፍል
ስጥኤማውያንም ፡ በዮናታን ፡ እጅ ፡ ወደቁ ፥
፲፬፤ ጋሻ ፡ ጃግሬውም ፡ ተከትሎ ፡ ገደላቸው ። የዮ
ናታንና ፡ የጋሻ ፡ ጃግሬውም ፡ የመጀመሪያ ፡
ግዳያቸው ፡ በአንድ ፡ ትልም ፡ እርሻ ፡ መካከል ፡
፲፭፤ ሀያ ፡ ያህል ፡ ሰው ፡ ነበረ ። በሰፈሩም ፡ በእርሻ
ውና ፡ በሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ ሽብር ፡
ነበረ ፤ በሰፈሩ ፡ የተቀመጡና ፡ ለምርኮ ፡ የወ
ጡት ፡ ተሸበሩ ፤ ምድሪቱም ፡ ተናወጠች ፤ ከእ
ግዚአብሔርም ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡ ሽብር ፡ ሆነ ።
፲፮፤ በብንያም ፡ ጊብዓ ፡ ያሉ ፡ የሳኦል ፡ ዘበኞችም ፡
ተመለከቱ ፤ እነሆም ፥ ሠራዊቱ ፡ ወዲህና ፡
፲፯፤ ወዲያ ፡ እየተራወጡ ፡ ተበታተኑ ። ሳኦልም ፡
ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩትን ፡ ሕዝብ ፡— እስኪ ፡
ተቋጠሩ ፥ ከእኛ ፡ ዘንድ ፡ የሄደ ፡ ማን ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ ተመልከቱ ፡ አላቸው ። በተቋጠሩም ፡ ጊዜ ፡
እነሆ ፥ ዮናታንና ፡ ጋሻ ፡ ጃግሬው ፡ በዚያ ፡ አል
፲፰፤ ነበሩም ። በዚያም ፡ ቀን ፡ አኪያ ፡ በእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ፊት ፡ ኤፉድ ፡ ለብሶ ፡ ነበርና ፡ ሳኦል ፡—
፲፱፤ ኤፉድን ፡ አምጣ ፡ አለው ። ሳኦል ፡ ከካህኑ ፡
ጋር ፡ ሲነጋገር ፡ በፍልስጥኤማውያን ፡ ሰፈር ፡
ግርግርታ ፡ እየበዛና ፡ እየጠነከረ ፡ ሄደ ፤ ሳኦ
ልም ፡ ካህኑን ፡— እጅህን ፡ መልስ ፡ አለው ።
፳፤ ሳኦልና ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ ሕዝብ ፡
ሁሉ ፡ ተሰብስበው ፡ ወደ ፡ ውጊያው ፡ መጡ ፤
እነሆም ፥ የእያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ ሰይፍ ፡ በባልንጀ
ራው ፡ ላይ ፡ ነበረ ፥ እጅግም ፡ ታላቅ ፡ ድንጋጤ ፡
፳፩፤ ሆነ ። ቀድሞ ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ ጋር ፡ የነ
በሩት ፡ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ከሰፈሩ ፡ ዙሪያ ፡ የወ
ጡት ፡ ዕብራውያን ፡ ደግሞ ፡ ከሳኦልና ፡ ከዮና
ታን ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ነበሩት ፡ እስራኤላውያን ፡ ለመ
፳፪፤ ሆን ፡ ዞሩ ። ከእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ በተራራ
ማው ፡ በኤፍሬም ፡ አገር ፡ የተሸሸጉት ፡ ሁሉ ፡
ፍልስጥኤማውያን ፡ እንደ ፡ ኰበለሉ ፡ በሰሙ ፡
ጊዜ ፡ እነርሱ ፡ ደግሞ ፡ ሊዋጉአቸው ፡ ተከት
፳፫፤ ለው ፡ ገሠገሡ ። እግዚአብሔርም ፡ በዚያ ፡
ቀን ፡ እስራኤልን ፡ አዳነ ፤ ውጊያውም ፡ በቤት
አዌን ፡ በኩል ፡ አለፈ ። ከሳኦልም ፡ ጋር ፡ የነ
በሩ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ የሚያህሉ ፡
ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ ውጊያውም ፡ በተራራማው ፡
በኤፍሬም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ተበታትኖ ፡ ነበር ።
፳፬፤ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ተጨነቁ ፤
ሳኦል ፡— ጠላቶቼን ፡ እስክበቀል ፡ እስከ ፡ ማታ ፡
ድረስ ፡ መብል ፡ የሚበላ ፡ ሰው ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፡
ብሎ ፡ ሕዝቡን ፡ አምሎአቸው ፡ ነበርና ። ሕዝ
፳፭፤ ቡም ፡ ሁሉ ፡ መብል ፡ አልቀመሱም ። ሕዝ
ቡም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ዱር ፡ ገባ ፤ ማርም ፡ በም
፳፮፤ ድር ፡ ላይ ፡ ነበረ ። ሕዝቡም ፡ ወደ ፡ ዱር ፡ በገባ ፡
ጊዜ ፡ እነሆ ፥ የሚፈስስ ፡ ማር ፡ ነበረ ፤ ሕዝቡ ፡
መሐላውን ፡ ፈርቶ ፡ ነበርና ማንም ፡ እጁን ፡
፳፯፤ ወደ ፡ አፉ ፡ አላደረገም ። ዮናታን ፡ ግን ፡ አባቱ ፡
ሕዝቡን ፡ በማለ ፡ ጊዜ ፡ አልሰማም ፡ ነበር ፤ እር
ሱም ፡ በእጁ ፡ ያለችውን ፡ በትር ፡ ጫፍዋን ፡
ወደ ፡ ወለላው ፡ ነከረ ፥ እጁንም ፡ ወደ ፡ አፉ ፡
፳፰፤ አደረገ ፤ ዓይኑም ፡ በራ ። ከሕዝቡም ፡ አንድ ፡
ሰው ፡ መልሶ ፡— አባትህ ፡— ዛሬ ፡ መብል ፡ የሚ
በላ ፡ ሰው ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፡ ብሎ ፡ ሕዝቡን ፡
መሐላ ፡ አምሎአቸዋል ፡ አለው ፤ ሕዝቡም ፡
፳፱፤ ደከሙ ። ዮናታንም ፡— አባቴ ፡ ምድሪቱን ፡
አስቸገረ ፤ ከዚህ ፡ ማር ፡ ጥቂት ፡ ብቀምስ ፡
፴፤ ዓይኔ ፡ እንደ ፡ በራ ፡ እዩ ። ይልቅስ ፡ ሕዝቡ ፡
ካገኙት ፡ ከጠላቶቻቸው ፡ ምርኮ ፡ በልተው ፡
ቢሆኑ ፡ የፍልስጥኤማውያን ፡ መመታት ፡ ይበ
ልጥ ፡ አልነበረምን ? አለ ።
፴፩፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ፍልስጥኤማውያንን ፡ ከማክ
ማስ ፡ እስከ ፡ ኤሎን ፡ ድረስ ፡ መቱአቸው ፤ ሕዝ
፴፪፤ ቡም ፡ እጅግ ፡ ደከሙ ። ሕዝቡም ፡ ለምርኮ ፡
ሳሱ ፤ በጎችን ፡ በሬዎችንም ፡ ጥጆችንም ፡ ወስ
ደው ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አረዱ ፤ ሕዝቡም ፡
፴፫፤ ከደሙ ፡ ጋር ፡ በሉ ። ለሳኦልም ፡— እነሆ ፥
ሕዝቡ ፡ ከደሙ ፡ ጋር ፡ በመብላታቸው ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ በደሉ ፡ ብለው ፡ ነገሩት ። ሳኦልም ፡—
እጅግ ፡ ተላለፋችሁ ፤ አሁንም ፡ ትልቅ ፡ ድን
ጋይ ፡ አንከባልላችሁ ፡ አቅርቡልኝ ፡ አላቸው ።

፴፬፤ ሳኦልም ፡— በሕዝቡ ፡ መካከል ፡ እየዞራችሁ ፡—
እያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ በሬውንና ፡ በጉን ፡ ወደ ፡
እኔ ፡ ያቅርብ ÷ በዚህም ፡ እረዱና ፡ ብሉ ፤ ከደ
ሙም ፡ ጋር ፡ በመብላታችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡
አትበድሉ ፡ በሉአቸው ፡ አለ ። እያንዳንዱም ፡
ሰው ፡ ሁሉ ፡ በእጁ ፡ ያለውን ፡ በሬውን ፡ በዚ
ያች ፡ ሌሊት ፡ አቀረበ ÷ በዚያም ፡ አረደው ።
፴፭፤ ሳኦልም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠዊያን ፡ ሠራ ፤
ይኸውም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሠራው ፡ መጀ
መሪያ ፡ መሠዊያ ፡ ነው ።
፴፮፤ ሳኦልም ፡— ፍልስጥኤማውያንን ፡ በሌሊት ፡
ተከትለን ፡ እስኪነጋ ፡ ድረስ ፡ እንበዝብዛቸው ፤
አንድ ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ አናስቀርላቸው ፡ አለ ።
እነርሱም ፡— ደስ ፡ የሚያሰኝህን ፡ ሁሉ ፡ አድ
ርግ ፡ አሉት ። ካህኑም ፡— ወደ ፡ እግዚአብ
፴፯፤ ሔር ፡ እንቅረብ ፡ አለ ። ሳኦልም ፡— ፍልስጥ
ኤማውያንን ፡ ልከተልን ? በእስራኤልስ ፡ እጅ ፡
አሳልፈህ ፡ ትሰጣቸዋለህን ? ብሎ ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ ጠየቀው ። በዚያ ፡ ቀን ፡ ግን ፡ አልመ
፴፰፤ ለሰለትም ። ሳኦልም ፡— እናንተ ፡ የሕዝቡ ፡
አለቆች ፡ ሁሉ ÷ ወደዚህ ፡ ቅረቡ ፤ ዛሬ ፡ ይህ ፡
ኃጢአት ፡ በምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እወቁ ÷ ተመ
፴፱፤ ልከቱም ፤ እስራኤልን ፡ የሚያድን ፡ ሕያው ፡
እግዚአብሔርን ! ኃጢአቱ ፡ በልጄ ፡ በዮናታን ፡
ቢሆን ፡ ፈጽሞ ፡ ይሞታል ፡ አለ ። ከሕዝቡም ፡
ሁሉ ፡ አንድ ፡ የመለሰለት ፡ ሰው ፡ አልነበረም ።
፵፤ እስራኤልንም ፡ ሁሉ ፡— እናንተ ፡ በአንድ ፡
ወገን ፡ ሁኑ ÷ እኔና ፡ ልጄ ፡ ዮናታንም ፡ በሌላ ፡
ወገን ፡ እንሆናለን ፡ አለ ። ሕዝቡም ፡ ሳኦልን ፡—
፵፩፤ ደስ ፡ የሚያሰኝህን ፡ አድርግ ፡ አሉት ። ሳኦልም ፡
የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡—
እውነትን ፡ ግለጥ ፡ አለው ። ሳኦልና ፡ ዮናታ
፵፪፤ ንም ፡ ተያዙ ፤ ሕዝቡም ፡ ነጻ ፡ ሆነ ። ሳኦልም ፡—
በእኔና ፡ በልጄ ፡ በዮናታን ፡ መካከል ፡ ዕጣ ፡
ጣሉ ፡ አለ ። ዮናታንም ፡ ተያዘ ።
፵፫፤ ሳኦልም ፡ ዮናታንን ፡— ያደረግኸውን ፡ ንገ
ረኝ ፡ አለው ፤ ዮናታንም ፡— በእጄ ፡ ባለው ፡
በበትሬ ፡ ጫፍ ፡ ጥቂት ፡ ማር ፡ በእርግጥ ፡ ቀም
ሻለሁ ፤ እነሆኝ ÷ እሞታለሁ ፡ ብሎ ፡ ነገረው ።
፵፬፤ ሳኦልም ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ያድርግ
ብኝ ፡ እንዲህም ፡ ይጨምርብኝ ፤ ዮናታን ፡
፵፭፤ ሆይ ÷ ፈጽመህ ፡ ትሞታለህ ፡ አለ ። ሕዝቡም ፡
ሳኦልን ፡— በውኑ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡
መድኃኒት ፡ ያደረገ ፡ ዮናታን ፡ ይሞታልን ?
ይህ ፡ አይሁን ፤ ዛሬ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡
አድርጎአልና ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! ከራሱ ፡
ጠጕር ፡ አንዲት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አትወድ
ቅም ፡ አሉት ። ሕዝቡም ፡ እንዳይሞት ፡ ዮና
፵፮፤ ታንን ፡ አዳነው ። ሳኦልም ፡ ፍልስጥኤማውያ
ንን ፡ ከመከተል ፡ ተመለሰ ፤ ፍልስጥኤማውያ
ንም ፡ ወደ ፡ ስፍራቸው ፡ ሄዱ ።
፵፯፤ ሳኦልም ፡ መንግሥቱን ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡
አጸና ፤ በዙሪያውም ፡ ካሉት ፡ ከጠላቶቹ ፡
ሁሉ ፡ ጋር ÷ ከሞዓብም ÷ ከአሞንም ፡ ልጆች ÷
ከኤዶምያስም ÷ ከሱባም ፡ ነገሥታት ÷ ከፍል
ስጥኤማውያንም ፡ ጋር ፡ ይዋጋ ፡ ነበር ፤ በየሄደ
፵፰፤ በትም ፡ ሁሉ ፡ ድል ፡ ይነሣ ፡ ነበር ። እርሱም ፡
ጀግና ፡ ነበረ ÷ አማሌቃውያንንም ፡ መታ ÷
እስራኤልንም ፡ ከዘራፊዎቹ ፡ እጅ ፡ አዳነ ።
፵፱፤ የሳኦልም ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ ዮናታን ÷
የሱዊ ÷ ሜልኪሳ ፡ ነበሩ ፤ የሁለቱም ፡ ሴቶች ፡
ልጆቹ ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነበረ ፤ የታላቂቱ ፡ ስም ፡
ሜሮብ ÷ የታናሺቱም ፡ ስም ፡ ሜልኮል ፡ ነበረ ።
፶፤ የሳኦልም ፡ ሚስት ፡ ስም ፡ የአኪማአስ ፡ ልጅ ፡
አኪናሆም ፡ ነበረ ፤ የሠራዊቱም ፡ አለቃ ፡ ስም ፡
የሳኦል ፡ አጎት ፡ የኔር ፡ ልጅ ፡ አበኔር ፡ ነበረ ።
፶፩፤ የሳኦልም ፡ አባት ፡ ቂስ ፡ ነበረ ፤ የአበኔርም ፡
አባት ፡ ኔር ፡ የአቢኤል ፡ ልጅ ፡ ነበረ ።
፶፪፤ በሳኦልም ፡ ዕድሜ ፡ ሁሉ ፡ ከፍልስጥኤማው
ያን ፡ ጋር ፡ ጽኑ ፡ ውጊያ ፡ ነበረ ፤ ሳኦልም ፡
ጽኑ ፡ ወይም ፡ ኃያል ፡ ሰው ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡
እርሱ ፡ ይሰበስብ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩፤ ሳሙኤልም ፡ ሳኦልን ፡ አለው ፡— በሕዝቡ ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ እንድትሆን ፡ እቀ
ባህ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ላከኝ ÷ አሁንም ፡
፪፤ የእግዚአብሔርን ፡ ድምፅ ፡ ስማ ። የሠራዊት ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እስራ
ኤል ፡ ከግብጽ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ አማሌቅ ፡ በመን
ገድ ፡ እየተቃወመ ፡ ያደረገበትን ፡ እበቀላለሁ ።
፫፤ አሁንም ፡ ሄደህ ፡ አማሌቅን ፡ ምታ ÷ ያላቸው
ንም ፡ ሁሉ ፡ ፈጽመህ ፡ አጥፋ ÷ አትማራቸውም ፤
ወንዱንና ፡ ሴቱን ፡ ብላቴናውንና ፡ ሕፃኑን ፡ በሬ
ውንና ፡ በጉን ፡ ግመሉንና ፡ አህያውን ፡ ግደል ።
፬፤ ሳኦልም ፡ ሕዝቡን ፡ ጠርቶ ፡ በጌልገላ ፡ ቈጠ
ራቸው ፤ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ እግረኞች ÷ ከይ
፭፤ ሁዳም ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ። ሳኦልም ፡
ወደ ፡ አማሌቅ ፡ ከተማ ፡ ወጣ ÷ በሸለቆውም ፡
፮፤ ውስጥ ፡ ተደበቀ ። ሳኦል ፡ ቄናውያንን ፡— ተነ
ሥታችሁ ፡ ሂዱ ፤ ከግብጽ ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፡ ለእ
ስራኤል ፡ ልጆች ፡ ቸርነት ፡ አድርጋችኋልና ፡
ከአማሌቅ ፡ ጋር ፡ እንዳላጠፋችሁ ፡ ከመካከላ
ቸው ፡ ውረዱ ፡ አላቸው ፤ ቄናውያንም ፡ ከአ
፯፤ ማሌቃውያን ፡ መካከል ፡ ሄዱ ። ሳኦልም ፡ አማ
ሌቃውያንን ፡ ከኤውላጥ ፡ ጀምሮ ፡ በግብጽ ፡
ፊት ፡ እስካለችው ፡ እስከ ፡ ሱር ፡ ድረስ ፡ መታ
፰፤ ቸው ። የአማሌቅንም ፡ ንጉሥ ፡ አጋግን ፡ በሕ
ይወቱ ፡ ማረከው ÷ ሕዝቡንም ፡ ሁሉ ፡ በሰይፍ ፡
፱፤ ስለት ፡ ፈጽሞ ፡ አጠፋቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ ሳኦ
ልና ፡ ሕዝቡ ፡ ለአጋግ ÷ ለተመረጡትም ፡ በጎ
ችና ፡ በሬዎች ፡ ለሰቡትም ፡ ጥጆችና ፡ ጠቦቶች ÷
ለመልካሞቹም ፡ ሁሉ ፡ ራሩላቸው ÷ ፈጽሞ ፡
ሊያጠፉአቸውም ፡ አልወደዱም ፤ ነገር ፡ ግን ፡
ምናምንቴንና ፡ የተናቀውን ፡ ሁሉ ፡ ፈጽመው ፡
አጠፉት ።
፲ ፡ ፲፩፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡— ሳኦል ፡ እኔን ፡
ከመከተል ፡ ተመልሶአልና ÷ ትእዛዜንም ፡ አል

ፈጸመምና ፡ ስላነገሥሁት ፡ ተጸጸትሁ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ሳሙኤል ፡ መጣ ። ሳሙኤልም ፡ ተቈጣ ፤ ሌሊቱንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኸ ።

፲፪ ሳሙኤልም ፡ በነጋው ፡ ሳኦልን ፡ ለመገናኘት ፡ ማለደ ፡— ሳኦልም ፡ ወደ ፡ ቀርሚሎስ ፡ መጣ ፤ እነሆም ፥ የመታሰቢያ ፡ ዓምድ ፡ በቆመ ፡ ጊዜ ፡ ዞሮ ፡ አለፈ ፥ ወደ ፡ ጌልገላም ፡ ወረደ ፡ የሚል ፡ ወሬ ፡ ለሳሙኤል ፡ ደረሰለት ።

፲፫ ሳሙኤልም ፡ ወደ ፡ ሳኦል ፡ መጣ ፤ ሳኦልም ፡— አንተ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተባረክህ ፡ ሁን ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ፈጽሜአለሁ ፡ አለው ።

፲፬ ሳሙኤልም ፡— ይህ ፡ በጆሮዬ ፡ የምሰማው ፡ የበጎች ፡ ጩኸትና ፡ የበሬዎች ፡ ግሣት ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለ ።

፲፭ ሳኦልም ፡— ሕዝቡ ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይሠዉአቸው ፡ ዘንድ ፡ መልካሞቹን ፡ በጎችና ፡ በሬዎች ፡ አድነዋቸዋልና ፡ ከአማሌቃውያን ፡ አምጥተዋቸዋል ፤ የቀሩትንም ፡ ፈጽመን ፡ አጠፋን ፡ አለው ።

፲፮ ሳሙኤልም ፡ ሳኦልን ፡— ቆይ ፥ እግዚአብሔር ፡ ዛሬ ፡ ሌሊት ፡ የነገረኝን ፡ ልንገርህ ፡ አለው ፤ እርሱም ፡— ተናገር ፡ አለው ።

፲፯ ሳሙኤልም ፡ አለ ፡— በዓይንህ ፡ ምንም ፡ ታናሽ ፡ ብትሆን ፡ ለእስራኤል ፡ ነገዶች ፡ አለቃ ፡ አልሆንህምን ? እግዚአብሔርም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ቀባህ ።

፲፰ እግዚአብሔርም ፡— ሂድህ ፡ ኃጢአተኞቹን ፡ አማሌቃውያንን ፡ ፈጽመህ ፡ አጥፋቸው ፥ እስኪጠፉም ፡ ድረስ ፡ ውጋቸው ፡ ብሎ ፡ በመንገድ ፡ ላከህ ።

፲፱ ለምርኮ ፡ ሳስተህ ፡ ለምን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አልሰማህም ? ለምንስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረግህ ?

፳ ሳኦልም ፡ ሳሙኤልን ፡— የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ሰምቻለሁ ፥ እግዚአብሔርም ፡ በላከኝ ፡ መንገድ ፡ ሄጃለሁ ፤ የአማሌቅን ፡ ንጉሥ ፡ አጋግን ፡ አምጥቻለሁ ፥ አማሌቃውያንንም ፡ ፈጽሜ ፡ አጥፍቻለሁ ።

፳፩ ሕዝቡ ፡ ግን ፡ ለአምላክህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በጌልገላ ፡ ይሠዉ ፡ ዘንድ ፡ ከእርሙ ፡ የተመረጡትን ፡ በጎችንና ፡ በሬዎችን ፡ ከምርኮው ፡ ወሰዱ ፡ አለው ።

፳፪ ሳሙኤልም ፡— በውኑ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ በመስማት ፡ ደስ ፡ እንደሚለው ፡ እግዚአብሔር ፡ በሚቃጠልና ፡ በሚታረድ ፡ መሥዋዕት ፡ ደስ ፡ ይለዋልን ? እነሆ ፥ መታዘዝ ፡ ከመሥዋዕት ፥ ማዳመጥም ፡ የአውራ ፡ በግ ፡ ስብ ፡ ከማቅረብ ፡ ይበልጣል ።

፳፫ ዓመፀኝነት ፡ እንደ ፡ ምዋርተኛ ፡ ኃጢአት ፥ እልከኝነትም ፡ ጣዖትንና ፡ ተራፊምን ፡ እንደ ፡ ማምለክ ፡ ነው ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ንቀሃልና ፡ እግዚአብሔር ፡ ንጉሥ ፡ እንዳትሆን ፡ ናቀህ ፡ አለ ።

፳፬ ሳኦልም ፡ ሳሙኤልን ፡— ሕዝቡን ፡ ስለ ፡ ፈራሁ ፥ ቃላቸውንም ፡ ስለ ፡ ሰማሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝና ፡ የአንተን ፡ ቃል ፡ በመተላለፍ ፡ በድያለሁ ።

፳፭ አሁንም ፥ እባክህ ፥ ኃጢአቴን ፡ ይቅር ፡ በለኝ ፥ ለእግዚአብሔርም ፡ እሰግድ ፡ ዘንድ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ተመለስ ፡ አለው ።

፳፮ ሳሙኤልም ፡ ሳኦልን ፡— የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ንቀሃልና ፥ እግዚአብሔርም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ እንዳትሆን ፡ ንቆሃልና ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አልመለስም ፡ አለው ።

፳፯ ሳሙኤልም ፡ ሊሄድ ፡ ዘወር ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ሳኦል ፡ የልብሱን ፡ ጫፍ ፡ ያዘ ፥ ተቀደደም ።

፳፰ ሳሙኤልም ፡— እግዚአብሔር ፡ የእስራኤልን ፡ መንግሥት ፡ ዛሬ ፡ ከአንተ ፡ ቀደዳት ፥ ከአንተም ፡ ለሚሻል ፡ ለጎረቤትህ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣት ፤

፳፱ የእስራኤል ፡ ኃይል ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ የሚጸጸት ፡ አይደለምና ፡ አይዋሽም ፡ አይጸጸትምም ፡ አለው ።

፴ እርሱም ፡— በድያለሁ ፤ አሁን ፡ ግን ፡ በሕዝቤ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ፊትና ፡ በእስራኤል ፡ ፊት ፥ እባክህ ፥ አክብረኝ ፤ ለአምላክህም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እሰግድ ፡ ዘንድ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ተመለስ ፡ አለው ።

፴፩ ሳሙኤልም ፡ ከሳኦል ፡ በኋላ ፡ ተመለሰ ፤ ሳኦልም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰገደ ።

፴፪ ሳሙኤልም ፡— የአማሌቅን ፡ ንጉሥ ፡ አጋግን ፡ አምጡልኝ ፡ አለ ። አጋግም ፡ እየተንቀጠቀጠ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጣ ። አጋግም ፡— በውኑ ፡ ሞት ፡ እንደዚህ ፡ መራራ ፡ ነውን ? አለ ።

፴፫ ሳሙኤልም ፡— ሰይፍህ ፡ ሴቶችን ፡ ልጆች ፡ አልባ ፡ እንዳደረገቻቸው ፡ እንዲሁ ፡ እናትህ ፡ በሴቶች ፡ መካከል ፡ ልጅ ፡ አልባ ፡ ትሆናለች ፡ አለ ፤ ሳሙኤልም ፡ አጋግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በጌልገላ ፡ ቈራረጠው ።

፴፬ ሳሙኤልም ፡ ወደ ፡ አርማቴም ፡ ሄደ ፤ ሳኦልም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ወደ ፡ ጊብዓ ፡ ወጣ ።

፴፭ ሳሙኤልም ፡ እስከ ፡ ሞተበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ሳኦልን ፡ ለማየት ፡ ዳግመኛ ፡ አልሄደም ፥ ሳሙኤልም ፡ ለሳኦል ፡ አለቀሰ ፤ እግዚአብሔርም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ሳኦልን ፡ ስላነገሠ ፡ ተጸጸተ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ሳሙኤልን ፡— በእስራኤል ፡ ላይ ፡ እንዳይነግሥ ፡ ለናቅሁት ፡ ለሳኦል ፡ የምታለቅስለት ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ? በቀንድህ ፡ ዘይቱን ፡ ሞልተህ ፡ ሂድ ፤ በልጆቹ ፡ መካከል ፡ ንጉሥ ፡ አዘጋጅቻለሁና ፡ ወደ ፡ እሴይ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፡ እልክሃለሁ ፡ አለው ።

፪ ሳሙኤልም ፡— እንዴት ፡ እሄዳለሁ ? ሳኦል ፡ ቢሰማ ፡ ይገድለኛል ፡ አለ ። እግዚአብሔርም ፡— አንዲት ፡ ጊደር ፡ ይዘህ ፡ ሂድና ፡— ለእግዚአብሔር ፡ እሠዋ ፡ ዘንድ ፡ መጥቻለሁ ፡ በል ።

፫ እሴይንም ፡ ወደ ፡ መሥዋዕቱ ፡ ጥራው ፥ የምታደርገውንም ፡ አስታውቅሃለሁ ፤ የምነግርህንም ፡ ቀባልኝ ፡ አለው ።

፬ ሳሙኤልም ፡ እግዚአብሔር ፡ የተናገረውን ፡ አደረገ ፥ ወደ ፡ ቤተ ፡ ልሔምም ፡ መጣ ። የአገሩም ፡ ሽማግሌዎች ፡ እየተንቀጠቀጡ ፡ ሊገናኙት ፡ መጡና ፡— የመጣኸው ፡ ለደኅንነት ፡ ነውን ? አሉት ።

፭ እርሱም ፡— ለደኅንነት ፡ ነው ፤ ለእግዚአብሔር ፡ እሠዋ ፡ ዘንድ ፡ መጥቻለሁ ፤ ቅዱሳን ፡ ሁኑ ፥ ከእ

ኔም ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ መሥዋዕቱ ፡ ኑ ፡ አለ ። እሴይንና ፡ ልጆቹንም ፡ ቀደሳቸው ÷ ወደ ፡ መሥዋዕቱም ፡ ጠራቸው ።

፮ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ኤልያብ ፡ ተመልክቶ ፡— በእውነት ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚቀበው ፡ በፊቱ ፡ ነው ፡ አለ ። ፯ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ሳሙኤልን ፡— ፊቱን ፡ የቁመቱንም ፡ ዘለግታ ፡ አትይ ፤ ሰው ፡ እንዲያይ ፡ እግዚአብሔር ፡ አያይምና ፡ ናቅሁት ፤ ሰው ፡ ፊትን ፡ ያያል ÷ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ልብን ፡ ያያል ፡ አለው ። ፰ እሴይም ፡ አሚናዳብን ፡ ጠርቶ ፡ በሳሙኤል ፡ ፊት ፡ አሳለፈው ፤ እርሱም ፡— ይህን ፡ ደግሞ ፡ ፱ እግዚአብሔር ፡ አልመረጠውም ፡ አለ ። እሴይም ፡ ሣማን ፡ አሳለፈው ፤ እርሱም ፡— ይህን ፡ ደግሞ ፡ እግዚአብሔር ፡ አልመረጠውም ፡ አለ ። ፲ እሴይም ፡ ከልጆቹ ፡ ሰባቱን ፡ በሳሙኤል ፡ ፊት ፡ አሳለፋቸው ። ሳሙኤልም ፡ እሴይን ፡— እግዚአብሔር ፡ እነዚህን ፡ አልመረጠም ፡ አለው ። ፲፩ ሳሙኤልም ፡ እሴይን ፡— የቀረ ፡ ሌላ ፡ ልጅ ፡ አለህን ? አለው ። እርሱም ፡— ታናሹ ፡ ገና ፡ ቀርቶአል ፤ እነሆም ÷ በጎችን ፡ ይጠብቃል ፡ አለ ። ሳሙኤልም ፡ እሴይን ፡— እርሱ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ አንረፍቅምና ፡ ልከህ ፡ አስመጣው ፡ ፲፪ አለው ። ልኮም ፡ አስመጣው ፤ እርሱም ፡ ቀይ ÷ ዓይኑም ፡ የተዋበ ÷ መልኩም ፡ ያማረ ፡ ነበረ ። እግዚአብሔርም ፡— ይህ ፡ ነውና ፡ ተነሥተህ ፡ ፲፫ ቅበው ፡ አለ ። ሳሙኤልም ፡ የዘይቱን ፡ ቀንድ ፡ ወስዶ ፡ በወንድሞቹ ፡ መከከል ፡ ቀባው ። የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ ከዚያ ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ በዳዊት ፡ ላይ ፡ በኃይል ፡ መጣ ። ሳሙኤልም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ አርማቴም ፡ ሄደ ።

፲፬ የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ ከሳኦል ፡ ራቀ ÷ ክፉም ፡ መንፈስ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ፲፭ አሠቃየው ። የሳኦልም ፡ ባሪያዎች ፡— እነሆ ÷ ክፉ ፡ መንፈስ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ፲፮ ያሠቃይሃል ፤ በገና ፡ መልከም ፡ አድርጎ ፡ የሚመታ ፡ ሰው ፡ ይሹ ፡ ዘንድ ፡ ጌታችን ፡ በፊቱ ፡ የሚቆሙትን ፡ ባሪያዎቹን ፡ ይዘዝ ፤ ከእግዚአብሔርም ፡ ዘንድ ፡ ክፉ ፡ መንፈስ ፡ በሆነብህ ፡ ጊዜ ፡ በእጁ ፡ ሲመታ ፡ አንተ ፡ ደኅና ፡ ትሆናለህ ፡ ፲፯ አሉት ። ሳኦልም ፡ ባሪያዎቹን ፡— መልከም ፡ አድርጎ ፡ በገና ፡ መምታት ፡ የሚችል ፡ ሰው ፡ ፲፰ ፈልጋችሁ ፡ አምጡልኝ ፡ አላቸው ። ከብላቴኖቹም ፡ አንዱ ፡ መልሶ ፡— እነሆ ÷ መልከም ፡ አድርጎ ፡ በገና ፡ የሚመታ ፡ የቤተ ፡ ልሔማዊውን ፡ የእሴይን ፡ ልጅ ፡ አይቻለሁ ፤ እርሱም ፡ ጽኑዕ ፡ ኃያል ፡ ነው ÷ በነገርም ፡ ብልህ ÷ መልኩም ፡ ያማረ ፡ ነው ÷ እግዚአብሔርም ፡ ከእርሱ ፡ ፲፱ ጋር ፡ ነው ፡ አለ ። ሳኦልም ፡ ወደ ፡ እሴይ ፡ መልክተኞች ፡ ልኮ ፡— ከበጎች ፡ ጋር ፡ ያለውን ፡ ፳ ልጅህን ፡ ዳዊትን ፡ ላክልኝ ፡ አለ ። እሴይም ፡ እንጀራና ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ አቁማዳ ፡ የተጫነ ፡ አህያ ፡ የፍየልም ፡ ጠቦት ፡ ወስዶ ፡ በልጁ ፡ በዳ ፳፩ ዊት ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ ሳኦል ፡ ላከ ። ዳዊትም ፡ ወደ ፡ ሳኦል ፡ መጣ ÷ በፊቱም ፡ ቆመ ፤ እጅግም ፡ ወደደው ÷ ለእርሱም ፡ ጋሻ ፡ ጃግሬው ፡ ሆነ ። ፳፪ ሳኦልም ፡ ወደ ፡ እሴይ ፡— በዓይኔ ፡ ሞገስ ፡ አግኝቶአልና ፡ ዳዊት ፡ በፊቴ ÷ እባክህ ÷ ይቁም ፡ ብሎ ፡ ላከ ። ፳፫ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ክፉ ፡ መንፈስ ፡ በሳኦል ፡ ላይ ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ዳዊት ፡ በገና ፡ ይዞ ፡ በእጁ ፡ ይመታ ፡ ነበር ፤ ሳኦልንም ፡ ደስ ፡ ያሰኘው ፡ ያሳርፈውም ፡ ነበር ÷ ክፉ ፡ መንፈስም ፡ ከእርሱ ፡ ይርቅ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ጭፍሮቻቸውን ፡ በይሁዳ ፡ ባለው ፡ በሰኰት ፡ አከማቹ ፤ በሰኰትና ፡ በዓዜቃ ፡ መከከል ፡ በኤፌስደሚም ፡ ሰፈሩ ። ፪ ሳኦልና ፡ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ተከማቹ ÷ በዔላ ፡ ሸለቆም ፡ ሰፈሩ ÷ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ ጋር ፡ ሊዋጉ ፡ ተሰለፉ ። ፫ ፍልስጥኤማውያንም ፡ በአንድ ፡ ወገን ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ ቆመው ፡ ነበር ÷ እስራኤልም ፡ በሌላው ፡ ወገን ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ ቆመው ፡ ነበር ፤ በመከከላቸውም ፡ ሸለቆ ፡ ነበረ ። ፬ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ ሰፈር ፡ የጌት ፡ ሰው ፡ ጎልያድ ÷ ቁመቱም ፡ ስድስት ፡ ክንድ ፡ ከስንዝር ፡ የሆነ ÷ ዋነኛ ፡ ጀግና ፡ መጣ ። ፭ በራሱም ፡ የናስ ፡ ቍር ፡ ደፍቶ ፡ ነበር ÷ ጥሩርም ፡ ለብሶ ፡ ነበር ፤ የጥሩሩም ፡ ሚዛን ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ሰቅል ፡ ናስ ፡ ነበረ ። ፮ በእግሮቹም ፡ ላይ ፡ የናስ ፡ ገምባሌ ፡ ነበረ ÷ የናስም ፡ ጭሬ ፡ በትከሻው ፡ ላይ ፡ ነበረ ። ፯ የጦሩም ፡ የበ ፡ እንደ ፡ ሸማኔ ፡ መጠቅለያ ፡ ነበረ ፤ የጦሩም ፡ ሚዛን ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ሰቅል ፡ ብረት ፡ ነበረ ፤ ጋሻ ፡ ጃግሬውም ፡ በፊቱ ፡ ይሄድ ፡ ነበር ። ፰ እርሱም ፡ ቆሞ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ጭፍሮች ፡ ጮኸ ፡— ለሰልፍ ፡ ትሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ለምን ፡ ወጣችሁ ? እኔ ፡ ፍልስጥኤማዊ ÷ እናንተም ፡ የሳኦል ፡ ባሪያዎች ፡ አይደላችሁምን ? ለእናንተ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ምረጡ ÷ ወደ ፡ እኔም ፡ ይውረድ ፤ ፱ ከእኔም ፡ ጋር ፡ ሊዋጋ ፡ ቢችል ፡ ቢገድለኝም ÷ ባሪያዎች ፡ እንሆናችኋለን ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ባሸንፈው ፡ ብገድለውም ÷ እናንተ ፡ ባሪያዎች ፡ ትሆኑናላችሁ ÷ ለእኛም ፡ ትገዛላችሁ ፡ አለ ። ፲ ፍልስጥኤማዊውም ፡— ዛሬ ፡ የእስራኤልን ፡ ጭፍሮች ፡ ተገዳደርኋቸው ፤ እንዋጋ ፡ ዘንድ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ስጡኝ ፡ አለ ። ፲፩ ሳኦልና ፡ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ የሚላቸውን ፡ የፍልስጥኤማዊውን ፡ ቃል ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ፈሩ ÷ ደነገጡም ።

፲፪ ዳዊትም ፡ የዚያ ፡ የኤፍራታዊው ፡ ሰው ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፤ ያም ፡ ሰው ፡ ከቤተ ፡ ልሔም ፡ ይሁዳ ፡ ስሙም ፡ እሴይ ፡ ነበረ ፤ ስምንትም ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ፤ በሳኦልም ፡ ዘመን ፡ በዕድሜ ፡ አርጅቶ ፡ ሽምግሎም ፡ ነበር ። ፲፫ የእሴይም ፡ ሦስቱ ፡ ታላላቆች ፡ ልጆቹ ፡ ሳኦልን ፡ ተከትለው ፡ ወደ ፡ ሰልፉ ፡ ሄደው ፡ ነበር ፤ ወደ ፡ ሰልፉም ፡ የሄዱት ፡ የሦስቱ ፡ ልጆቹ ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነበረ ፤ ታላቁ ፡

ኤልያብ ፡ ሁለተኛው ፡ አሚናዳብ ፡ ሦስተኛ
፲፬ ውም ፡ ሣማ ፡ ነበረ ። ዳዊት ፡ የሁሉ ፡ ታናሽ ፡
ነበረ ፤ ሦስቱም ፡ ታላላቆች ፡ ሳኦልን ፡ ተከት
፲፭ ለው ፡ ነበር ። ዳዊትም ፡ የአባቱን ፡ በጎች ፡ ለመ
ጠበቅ ፡ ከሳኦል ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፡
፲፮ ይመላለስ ፡ ነበር ። ፍልስጥኤማዊውም ፡ ጥዋ
ትና ፡ ማታ ፡ ይቀርብ ፥ አርባ ፡ ቀንም ፡ ይታይ ፡
ነበር ።

፲፯ እሴይም ፡ ልጁን ፡ ዳዊትን ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡—
ከዚህ ፡ ከተጠበሰው ፡ እሸት ፡ አንድ ፡ የኢፍ ፡
መስፈሪያ ፡ እነዚህንም ፡ አሥር ፡ እንጀራዎች ፡
ለወንድሞችህ ፡ ውሰድ ፥ ወደ ፡ ሰፈሩም ፡ ወደ ፡
፲፰ ወንድሞችህ ፡ ፈጥነህ ፡ አድርሳቸው ፤ ይህንም ፡
አሥሩን ፡ አይብ ፡ ወደ ፡ ሻለቃው ፡ ውሰደው ፤
የወንድሞችህንም ፡ ደኅንነት ፡ ጠይቅ ፥ ወሬአ
፲፱ ቸውንም ፡ አምጣልኝ ። ሳኦልና ፡ እነርሱ ፡ የእ
ስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ከፍልስጥኤማው
ያን ፡ ጋር ፡ እየተዋጉ ፡ በኤላ ፡ ሸለቆ ፡ ነበሩ ።
፳ ዳዊትም ፡ ማልዶ ፡ ተነሣ ፥ በጎቹንም ፡ ለጠባቂ ፡
ተወ ፥ እሴይም ፡ ያዘዘውን ፡ ይዞ ፡ ሄደ ፤ ጭፍ
ራውም ፡ ተሰልፎ ፡ ሲወጣ ፡ ለሰልፍም ፡ ሲጮኽ ፡
በሰረገሎች ፡ ወደ ፡ ተከበበው ፡ ሰፈር ፡ መጣ ።
፳፩ እስራኤልና ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡
፳፪ ተሰላልፈው ፡ ነበር ። ዳዊትም ፡ ዕቃውን ፡
በዕቃ ፡ ጠባቂው ፡ እጅ ፡ አኖረው ፥ ወደ ፡ ሠራ
ዊቱም ፡ ሮጠ ፥ የወንድሞቹንም ፡ ደኅንነት ፡
፳፫ ጠየቀ ። እርሱም ፡ ሲነጋገራቸው ፥ እነሆ ፥ ጎል
ያድ ፡ የተባለው ፡ ያ ፡ ዋነኛ ፡ ጀግና ፡ ፍልስጥኤ
ማዊ ፡ የጌት ፡ ሰው ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡
ጭፍራ ፡ መካከል ፡ ወጣ ፥ የተናገረውንም ፡
፳፬ ቃል ፡ ተናገረ ፤ ዳዊትም ፡ ሰማ ። የእስራኤልም ፡
ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ሰውዮውን ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡
፳፭ ፈርተው ፡ ከእርሱ ፡ ሸሹ ። የእስራኤልም ፡
ሰዎች ፡— ይህን ፡ የወጣውን ፡ ሰው ፡ አያችሁ
ትን ? በእውነት ፡ እስራኤልን ፡ ሊገዳደር ፡ ወጣ ፤
የሚገድለውንም ፡ ሰው ፡ ንጉሡ ፡ እጅግ ፡ ባለ
ጠጋ ፡ ያደርገዋል ፥ ልጁንም ፡ ይድርለታል ፤
ያባቱንም ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡
፳፮ ከግብር ፡ ነጻ ፡ ያወጣቸዋል ፡ አሉ ። ዳዊትም ፡
በአጠገቡ ፡ ለቆሙት ፡ ሰዎች ፡— ይህን ፡ ፍልስ
ጥኤማዊ ፡ ለሚገድል ፥ ከእስራኤልም ፡ ተግዳ
ሮትን ፡ ለሚያርቅ ፡ ሰው ፡ ምን ፡ ይደረግለታል ?
የሕያውን ፡ አምላክ ፡ ጭፍሮች ፡ የሚገዳደር ፡
ይህ ፡ ያልተገረዘ ፡ ፍልስጥኤማዊ ፡ ማን ፡ ነው ?
፳፯ ብሎ ፡ ተናገራቸው ። ሕዝቡም ፡— ለሚገድ
ለው ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ይደረግለታል ፡ ብለው ፡
እንደ ፡ ቀድሞው ፡ መለሱለት ።

፳፰ ታላቅ ፡ ወንድሙም ፡ ኤልያብ ፡ ከሰዎች ፡
ጋር ፡ ሲነጋገር ፡ ሰማ ፤ የኤልያብም ፡ ቍጣ ፡ በዳ
ዊት ፡ ላይ ፡ ነድዶ ፡— ለምን ፡ ወደዚህ ፡ ወረ
ድህ ? እነዚያንስ ፡ ጥቂቶች ፡ በጎች ፡ በምድረ ፡
በዳ ፡ ለማን ፡ ተውሃቸው ? እኔ ፡ ኵራትህንና ፡
የልብህን ፡ ክፋት ፡ አውቃለሁና ፡ ሰልፉን ፡ ለማ
፳፱ የት ፡ መጥተሃል ፡ አለው ። ዳዊትም ፡— እኔ ፡
ምን ፡ አደረግሁ ? ይህ ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡ አይደለ
፴ ምን ? አለ ። ዳዊትም ፡ ከእርሱ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡
ሰው ፡ ዞወር ፡ አለ ፥ እንደዚህም ፡ ያለ ፡ ነገር ፡
ተናገረ ፤ ሕዝቡም ፡ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ያለ ፡
ነገር ፡ መለሱለት ።

፴፩ ዳዊትም ፡ የተናገረው ፡ ቃል ፡ ተሰማ ፥ ለሳኦ
ልም ፡ ነገሩት ፤ ወደ ፡ እርሱም ፡ አስጠራው ።
፴፪ ዳዊትም ፡ ሳኦልን ፡— ስለ ፡ እርሱ ፡ የማንም ፡
ልብ ፡ አይውደቅ ፤ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ሄጄ ፡ ያንን ፡
፴፫ ፍልስጥኤማዊ ፡ እወጋዋለሁ ፡ አለው ። ሳኦ
ልም ፡ ዳዊትን ፡— አንተ ፡ ገና ፡ ብላቴና ፡ ነህና ፥
እርሱም ፡ ከብላቴንነቱ ፡ ጀምሮ ፡ ጦረኛ ፡ ነውና ፡
ይህን ፡ ፍልስጥኤማዊ ፡ ለመውጋት ፡ ትሄድ ፡
፴፬ ዘንድ ፡ አትችልም ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ ሳኦ
ልን ፡ አለው ፡— እኔ ፡ ባሪያህ ፡ የአባቴን ፡ በጎች ፡
ስጠብቅ ፡ አንበሳና ፡ ድብ ፡ ይመጣ ፡ ነበር ፥ ከመ
፴፭ ንጋውም ፡ ጠቦት ፡ ይወስድ ፡ ነበር ። በኋላ
ውም ፡ እከተለውና ፡ እመታው ፡ ነበር ፥ ከአ
ፉም ፡ አስጥለው ፡ ነበር ፤ በተነሣብኝም ፡ ጊዜ ፡
ጕሮሮውን ፡ ይዤ ፡ እመታውና ፡ እገድለው ፡
፴፮ ነበር ። እኔ ፡ ባሪያህ ፡ አንበሳና ፡ ድብ ፡ መታሁ ፤
ይህም ፡ ያልተገረዘው ፡ ፍልስጥኤማዊ ፡ የሕያ
ውን ፡ አምላክ ፡ ጭፍሮች ፡ ተገዳድሮአልና ፡
፴፯ ከእነርሱ ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ይሆናል ። ዳዊትም ፡—
ከአንበሳና ፡ ከድብ ፡ እጅ ፡ ያስጣለኝ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ከዚህ ፡ ፍልስጥኤማዊ ፡ እጅ ፡ ያስጥለ
ኛል ፡ አለ ። ሳኦልም ፡ ዳዊትን ፡— ሂድ ፥ እግዚ
አብሔርም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይሆናል ፡ አለው ።
፴፰ ሳኦልም ፡ ዳዊትን ፡ የገዛ ፡ ራሱን ፡ ልብስ ፡ አለ
በሰው ፥ በራሱም ፡ ላይ ፡ የናስ ፡ ቍር ፡ ደፋ
፴፱ ለት ፥ ጥሩርም ፡ አለበሰው ። ዳዊትም ፡ ሰይፉን ፡
በልብሱ ፡ ላይ ፡ ታጠቀ ፥ ገናም ፡ አልፈተነው
ምና ፡ መሄድ ፡ ሞከረ ። ዳዊትም ፡ ሳኦልን ፡—
አልፈተንሁትምና ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ መሄድ ፡
፵ አልችልም ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ አወለቀ ። በት
ሩንም ፡ በእጁ ፡ ወሰደ ፥ ከወንዝም ፡ አምስት ፡
ድብልብል ፡ ድንጋዮችን ፡ መረጠ ፥ በእረኛ ፡
ኮረጆውም ፡ በኪሱ ፡ ከተታቸው ፤ ወንጭፍም ፡
በእጁ ፡ ነበረ ፤ ወደ ፡ ፍልስጥኤማዊውም ፡
ቀረበ ።

፵፩ ፍልስጥኤማዊውም ፡ መጥቶ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡
ቀረበ ፤ ጋሻ ፡ ጃግሬውም ፡ በፊቱ ፡ ይሄድ ፡ ነበር ።
፵፪ ጎልያድም ፡ ዳዊትን ፡ ትኵር ፡ ብሎ ፡ አየው ፤
ቀይ ፡ ብላቴና ፡ መልኩም ፡ ያማረ ፡ ነበረና ፡
፵፫ ናቀው ። ፍልስጥኤማዊውም ፡ ዳዊትን ፡—
በትር ፡ ይዘህ ፡ የምትመጣብኝ ፡ እኔ ፡ ውሻ ፡
ነኝን ? አለው ። ፍልስጥኤማዊውም ፡ በአምላ
፵፬ ኮቹ ፡ ስም ፡ ዳዊትን ፡ ረገመው ። ፍልስጥኤማዊ
ውም ፡ ዳዊትን ፡— ወደ ፡ እኔ ፡ ና ፥ ሥጋህንም ፡
ለሰማይ ፡ ወፎችና ፡ ለምድር ፡ አራዊት ፡ እሰጣ
፵፭ ለሁ ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ ፍልስጥኤማዊውን ፡
አለው ፡— አንተ ፡ ሰይፍና ፡ ጦር ፡ ጭሬም ፡ ይዘህ ፡
ትመጣብኛለህ ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ዛሬ ፡ በተገዳደር
ኸው ፡ በእስራኤል ፡ ጭፍሮች ፡ አምላክ ፡ ስም ፡

በሠራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ እመ
፵፮ ጣብሃለሁ ። እግዚአብሔር ፡ ዛሬ ፡ አንተን ፡ በእጄ ፡
አሳልፎ ፡ ይሰጣል ፤ እመታሀማለሁ ፥ ራስህንም ፡
ከአንተ ፡ እነሣዋለሁ ፤ የፍልስጥኤማውያንንም ፡
ሠራዊት ፡ ሬሶች ፡ ለሰማይ ፡ ወፎችና ፡ ለምድር ፡
አራዊት ፡ ዛሬ ፡ እሰጣለሁ ። ይኸውም ፡ ምድር ፡
ሁሉ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ አምላክ ፡ እንዳለ ፡
፵፯ ታውቅ ፡ ዘንድ ፤ ይህም ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ በሰይፍና ፡ በጦር ፡ የሚያድን ፡ እን
ዳይደለ ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ሰልፉ ፡ ለእግ
ዚአብሔር ፡ ነውና ፤ እናንተንም ፡ በእጃችን ፡
፵፰ አሳልፎ ፡ ይሰጣል ። ፍልስጥኤማዊውም ፡ ተነ
ሥቶ ፡ ዳዊትን ፡ ሊገናኘው ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፡
ዳዊት ፡ ፍልስጥኤማዊውን ፡ ሊገናኘው ፡ ወደ ፡
፵፱ ሰልፉ ፡ ሮጠ ። ዳዊትም ፡ እጁን ፡ ወደ ፡ ኮረ
ጆው ፡ አግብቶ ፡ አንድ ፡ ድንጋይ ፡ ወሰደ ፥
ወነጨፈውም ፥ ፍልስጥኤማዊውንም ፡ ግምባ
ሩን ፡ መታ ፤ ድንጋዩም ፡ በግምባሩ ፡ ተቀረቀረ ፥
እርሱም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በፊቱ ፡ ተደፋ ።

፶ ዳዊትም ፡ ፍልስጥኤማዊውን ፡ በወንጭፍና ፡
በድንጋይ ፡ አሸነፈው ፥ ፍልስጥኤማዊውንም ፡
መትቶ ፡ ገደለ ፤ በዳዊትም ፡ እጅ ፡ ሰይፍ ፡ አል
፶፩ ነበረም ። ዳዊትም ፡ ሮጦ ፡ በፍልስጥኤማዊው ፡
ላይ ፡ ቆመ ፤ ሰይፉንም ፡ ይዞ ፡ ከሰገባው ፡ መዘ
ዘው ፥ ገደለውም ፥ ራሱንም ፡ ቈረጠው ። ፍል
ስጥኤማውያንም ፡ ዋናቸው ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ በዩ ፡
፶፪ ጊዜ ፡ ሸሹ ። የእስራኤልና ፡ የይሁዳ ፡ ሰዎች ፡
ተነሥተው ፡ እልል ፡ አሉ ፥ ፍልስጥኤማውያ
ንንም ፡ እስከ ፡ ጌትና ፡ እስከ ፡ አስቀሎና ፡ በር
ድረስ ፡ አሳደዱአቸው ። ፍልስጥኤማውያንም ፡
ከሸዓራይም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ጌትና ፡ እስከ ፡
አቃሮን ፡ ድረስ ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ የተመቱት ፡
፶፫ ወደቁ ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ፍልስጥኤማ
ውያንን ፡ ከማሳደድ ፡ ተመልሰው ፡ ሰፈራቸ
፶፬ ውን ፡ በዘበዙ ። ዳዊትም ፡ የፍልስጥኤማዊ
ውን ፡ ራስ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ አመ
ጣው ፤ ጋሻ ፡ ጦሩን ፡ ግን ፡ በድንኳኑ ፡ ውስጥ ፡
አኖረው ።

፶፭ ሳኦልም ፡ ዳዊትን ፡ ወደ ፡ ፍልስጥኤማዊው ፡
ሲወጣ ፡ ባየው ፡ ጊዜ ፡ ለሠራዊቱ ፡ አለቃ ፡ ለአ
በኔር ፦ አበኔር ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡ ብላቴና ፡ የማን ፡
ልጅ ፡ ነው ? አለው ። አበኔርም ፦ ንጉሥ ፡
ሆይ ፥ በሕያው ፡ ነፍስህ ፡ እምላለሁ ፤ አላው
፶፮ ቅም ፡ አለ ። ንጉሡም ፦ ይህ ፡ ብላቴና ፡ የማን ፡
፶፯ ልጅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አንተ ፡ ጠይቅ ፡ አለ ። ዳዊ
ትም ፡ ፍልስጥኤማዊውን ፡ ገድሎ ፡ በተመለሰ ፡
ጊዜ ፡ አበኔር ፡ ወሰደው ፥ ወደ ፡ ሳኦልም ፡ ፊት ፡
አመጣው ፤ የፍልስጥኤማዊውንም ፡ ራስ ፡ በእጁ ፡
፶፰ ይዞ ፡ ነበር ። ሳኦልም ፦ አንተ ፡ ብላቴና ፥
የማን ፡ ልጅ ፡ ነህ ? አለው ። ዳዊትም ፦ እኔ ፡
የቤተ ፡ ልሔም ፡ የባሪያህ ፡ የእሴይ ፡ ልጅ ፡
ነኝ ፡ብሎ ፡ መለሰ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ ዳዊትም ፡ ለሳኦል ፡ መናገሩን ፡ በፈጸመ ፡
ጊዜ ፡ የዮናታን ፡ ነፍስ ፡ በዳዊት ፡ ነፍስ ፡ ታሰ
ረች ፥ ዮናታንም ፡ እንደ ፡ ነፍሱ ፡ ወደደው ።
፪ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሳኦል ፡ ወሰደው ፥ ወደ ፡ አባ
ቱም ፡ ቤት ፡ ይመልሰው ፡ ዘንድ ፡ አልተወውም ።
፫ ዮናታንም ፡ እንደ ፡ ነፍሱ ፡ ስለ ፡ ወደደው ፡ ከዳ
፬ ዊት ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረገ ። ዮናታንም ፡
የለበሰውን ፡ ካባ ፡ አውልቆ ፡ እርሱንና ፡ ልብ
ሱን ፡ ሰይፉንም ፡ ቀስቱንም ፡ መታጠቂያው
፭ ንም ፡ ለዳዊት ፡ ሸለመው ። ዳዊትም ፡ ሳኦል ፡
ወደ ፡ ሰደደው ፡ ሁሉ ፡ ይሄድ ፡ ነበር ፥ አስተው
ሎም ፡ ያደርግ ፡ ነበር ፤ ሳኦልም ፡ በጦረኞች ፡
ላይ ፡ ሾመው ፤ ይህም ፡ በሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ዓይ
ንና ፡ በሳኦል ፡ ባሪያዎች ፡ ዓይን ፡ መልካም ፡
ነበረ ።

፮ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ዳዊት ፡ ፍልስጥኤማዊውን ፡
ገድሎ ፡ በተመለሰ ፡ ጊዜ ፥ እየዘመሩና ፡ እየዘ
ፈኑ ፡ እልልም ፡ እያሉ ፡ ከበሮና ፡ እታሞ ፡ ይዘው ፡
ንጉሡን ፡ ሳኦልን ፡ ሊቀበሉ ፡ ሴቶች ፡ ከእስራ
፯ ኤል ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ወጡ ። ሴቶችም ፦
ሳኦል ፡ ሺህ ፥ ዳዊትም ፡ እልፍ ፡ ገደለ ፡ እያሉ ፡
፰ እየተቀባበሉ ፡ ይዘፍኑ ፡ ነበር ። ሳኦልም ፡ እጅግ ፡
ተቈጣ ፥ ይህም ፡ ነገር ፡ አስከፋው ፤ እርሱም ፦
ለዳዊት ፡ እልፍ ፡ ሰጡት ፥ ለእኔ ፡ ግን ፡ ሺህ ፡
ብቻ ፡ ሰጡኝ ፤ ከመንግሥት ፡ በቀር ፡ ምን ፡ ቀረ
፱ በት ? አለ ። ከዚያም ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ ሳኦል ፡
ዳዊትን ፡ ተመቅኝቶ ፡ ተመለከተው ።

፲ በነጋውም ፡ ሳኦልን ፡ ክፉ ፡ መንፈስ ፡ ከእግ
ዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ያዘው ፥ በቤቱም ፡ ውስጥ ፡
ትንቢት ፡ ተናገረ ። ዳዊትም ፡ በየቀኑ ፡ ያደርግ ፡
እንደ ፡ ነበረ ፡ በእጁ ፡ በገና ፡ ይመታ ፡ ነበር ። ሳኦ
፲፩ ልም ፡ ጦሩን ፡ በእጁ ፡ ይዞ ፡ ነበር ። ሳኦልም ፦
ዳዊትን ፡ ከግንቡ ፡ ጋር ፡ አጣብቄ ፡ እመታዋ
ለሁ ፡ ብሎ ፡ ጦሩን ፡ ወረወረ ። ዳዊትም ፡ ሁለት ፡
፲፪ ጊዜ ፡ ከፊቱ ፡ ዘወር ፡ አለ ። እግዚአብሔርም ፡ ከእ
ርሱ ፡ ጋር ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ከሳኦልም ፡ ስለ ፡ ተለየ ፡
፲፫ ሳኦል ፡ ዳዊትን ፡ ፈራው ። ስለዚህም ፡ ሳኦል ፡
ከእርሱ ፡ አራቀው ፥ የሺህ ፡ አለቃም ፡ አደረ
ገው ፤ በሕዝቡም ፡ ፊት ፡ ይወጣና ፡ ይገባ ፡ ነበር ።
፲፬ ዳዊትም ፡ በአካሄዱ ፡ ሁሉ ፡ አስተውሎ ፡ ያደ
ርግ ፡ ነበር ፤ እግዚአብሔርም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
፲፭ ነበረ ። ሳኦልም ፡ እጅግ ፡ ብልህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
፲፮ አይቶ ፡ እጅግ ፡ ፈራው ። ነገር ፡ ግን ፡ በፊታ
ቸው ፡ ይወጣና ፡ ይገባ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ እስራኤ
ልና ፡ ይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ ዳዊትን ፡ ወደዱ ።

፲፯ ሳኦልም ፡ ዳዊትን ፦ ታላቂቱ ፡ ልጄ ፡ ሜሮብ ፡
እነኋት ፤ እርስዋን ፡ እድርልሃለሁ ፤ ብቻ ፡ ቀል
ጣፋ ፡ ልጅ ፡ ሁንልኝ ፥ ስለ ፡ እግዚአብሔርም ፡
ጦርነት ፡ ተጋደል ፡ አለው ። ሳኦልም ፦ የፍል
ስጥኤማውያን ፡ እጅ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ትሁን ፡

እንጂ ፡ የእኔ ፡ እጅ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ አትሁን ፡ ይል ፡ ነበር ። ፲፰ ዳዊትም ፡ ሳኦልን ፡— ለንጉሥ ፡ አማች ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ እኔ ፡ ማን ፡ ነኝ ? ሰውነቴስ ፡ ምንድር ፡ ናት ? የአባቴስ ፡ ወገን ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለው ። ፲፱ ነገር ፡ ግን ፡ የሳኦል ፡ ልጅ ፡ ሜሮብ ፡ ዳዊትን ፡ የምታገባበት ፡ ጊዜ ፡ ሲደርስ ፡ ለመሓላታዊው ፡ ለኤስድሪኤል ፡ ተዳረች ። ፳ የሳኦልም ፡ ልጅ ፡ ሜልኮል ፡ ዳዊትን ፡ ወደደች ፤ ይህም ፡ ወሬ ፡ ለሳኦል ፡ ደረሰለት ÷ ነገሩም ፡ ደስ ፡ አሰኘው ። ፳፩ ሳኦልም ፡— ወጥመድ ፡ ትሆነው ፡ ዘንድ ÷ የፍልስጥኤማውያንም ፡ እጅ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ እርስዋን ፡ እድርለታለሁ ፡ አለ ፤ ሳኦልም ፡ ዳዊትን ፡— ዛሬ ፡ ሁለተኛ ፡ አማች ፡ ትሆነኛለህ ፡ አለው ።

፳፪ ሳኦልም ፡ ባሪያዎቹን ፡— እነሆ ÷ ንጉሥ ፡ እጅግ ፡ ወድዶሃል ÷ ባሪያዎቹም ፡ ሁሉ ፡ ወድደውሃል ÷ አሁንም ፡ ለንጉሥ ፡ አማች ፡ ሁን ፡ ብላችሁ ፡ በስውር ፡ ለዳዊት ፡ ንገሩት ፡ ብሎ ፡ ፳፫ አዘዛቸው ። የሳኦልም ፡ ባሪያዎች ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ በዳዊት ፡ ጆሮ ፡ ተናገሩ ፤ ዳዊትም ፡— እኔ ፡ ድሀ ፡ የተጠቃሁም ፡ ሰው ፡ ስሆን ፡ ለንጉሥ ፡ አማች ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ ለእናንተ ፡ ትንሽ ፡ ነገር ፡ ፳፬ ይመስላችኋልን ? አለ ። የሳኦልም ፡ ባሪያዎች ፡— ዳዊት ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ፡ ብለው ፡ ነገሩት ። ፳፭ ሳኦልም ፡ ዳዊትን ፡ በፍልስጥኤማውያን ፡ እጅ ፡ ይጥለው ፡ ዘንድ ፡ አስቦ ፡— የንጉሥን ፡ ጠላቶች ፡ ይበቀል ፡ ዘንድ ፡ ከመቶ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ሸለፈት ፡ በቀር ፡ ንጉሥ ፡ ማጫ ፡ አይሻም ፡ ብላችሁ ፡ ለዳዊት ፡ ንገሩት ፡ አላቸው ። ፳፮ የሳኦልም ፡ ባሪያዎች ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ለዳዊት ፡ ነገሩት ÷ ለንጉሥም ፡ አማች ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ፳፯ ዳዊትን ፡ ደስ ፡ አሰኘው ። ዳዊትና ፡ ሰዎቹም ፡ ተነሥተው ፡ ሄዱ ÷ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ገደሉ ፤ ዳዊትም ፡ ለንጉሥ ፡ አማች ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ሰለባቸውን ፡ አምጥቶ ፡ በቍጥራቸው ፡ ልክ ፡ ለንጉሡ ፡ ሰጠ ። ሳኦልም ፡ ልጁን ፡ ሜልኮልን ፡ ዳረለት ። ፳፰ ሳኦልም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከዳዊት ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አየ ፤ ፳፱ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ወደዱት ። ሳኦልም ፡ ዳዊትን ፡ አጥብቆ ፡ ፈራው ፤ ሳኦልም ፡ ዕድሜውን ፡ ሁሉ ፡ ለዳዊት ፡ ጠላት ፡ ሆነ ።

፴ የፍልስጥኤማውያንም ፡ አለቆች ፡ ይወጡ ፡ ነበር ፤ በወጡም ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ ከሳኦል ፡ ባሪያዎች ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ዳዊት ፡ አስተውሎ ፡ ያደርግ ፡ ነበርና ፡ ስሙ ፡ እጅግ ፡ ተጠርቶ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ ሳኦልም ፡ ለልጁ ፡ ለዮናታንና ፡ ለባሪያዎቹ ፡ ሁሉ ፡ ዳዊትን ፡ ይገድሉ ፡ ዘንድ ፡ ነገራቸው ። የሳኦል ፡ ልጅ ፡ ዮናታን ፡ ግን ፡ ዳዊትን ፡ እጅግ ፡ ፪ ይወድድ ፡ ነበር ። ዮናታንም ፡— አባቴ ፡ ሳኦል ፡ ሊገድልህ ፡ ፈልጎአል ፤ አሁን ፡ እንግዲህ ፡ ለነገው ፡ ተጠንቀቀህ ፡ ተሸሸግ ÷ በስውርም ፡ ተቀመጥ ፤ ፫ እኔም ፡ እወጣለሁ ፡ አንተም ፡ ባለህበት ፡ እርሻ ፡ በአባቴ ፡ አጠገብ ፡ እቆማለሁ ÷ ስለ ፡ አንተም ፡ ከአባቴ ፡ ጋር ፡ እነጋገራለሁ ፤ የሆነውንም ፡ አይቼ ፡ እነግርሃለሁ ፡ ብሎ ፡ ለዳዊት ፡ ነገረው ። ፬ ዮናታንም ፡ ለአባቱ ፡ ለሳኦል ፡— እርሱ ፡ አልበደለህምና ÷ ሥራውም ፡ ለአንተ ፡ እጅግ ፡ መልካም ፡ ሆኖአልና ፡ ንጉሡ ፡ ባሪያውን ፡ ዳዊትን ፡ አይበድለው ፤ ፭ ነፍሱንም ፡ በእጁ ፡ ጥሎ ፡ ፍልስጥኤማዊውን ፡ ገደለ ÷ እግዚአብሔርም ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ታላቅ ፡ መድኃኒት ፡ አደረገ ፤ አንተም ፡ አይተህ ፡ ደስ ፡ አለህ ፤ በከንቱ ፡ ዳዊትን ፡ በመግደልህ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ በንጹሕ ፡ ደም ፡ ላይ ፡ ትበድላለህ ? ብሎ ፡ ስለ ፡ ዳዊት ፡ መልካም ፡ ተናገረ ።

፮ ሳኦልም ፡ የዮናታንን ፡ ቃል ፡ ሰማ ፤ ሳኦልም ፡— ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! ዳዊት ፡ አይገደልም ፡ ብሎ ፡ ማለ ። ፯ ዮናታንም ፡ ዳዊትን ፡ ጠርቶ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ነገረው ፤ ዮናታንም ፡ ዳዊትን ፡ ወደ ፡ ሳኦል ፡ አመጣው ÷ እንደ ፡ ቀድሞውም ፡ በፊቱ ፡ ነበረ ።

፰ ደግሞም ፡ ጦርነት ፡ ሆነ ፤ ዳዊትም ፡ ወጥቶ ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ ጋር ፡ ተዋጋ ÷ ታላቅ ፡ ግዳይም ፡ ገደላቸው ÷ ከፊቱም ፡ ሸሹ ። ፱ ሳኦልም ፡ ጦሩን ፡ ይዞ ፡ በቤቱ ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፡ ክፉ ፡ መንፈስ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ያዘው ። ዳዊትም ፡ በእጁ ፡ በገና ፡ ይመታ ፡ ነበር ። ፲ ሳኦልም ፡ ዳዊትን ፡ ከግንብ ፡ ጋር ፡ ያጣብቀው ፡ ዘንድ ፡ ጦሩን ፡ ወረወረ ፤ ዳዊትም ፡ ከሳኦል ፡ ፊት ፡ ዘወር ፡ አለ ÷ ጦሩም ፡ በግንቡ ፡ ውስጥ ፡ ተተከለ ፤ በዚያም ፡ ሌሊት ፡ ዳዊት ፡ ሸሽቶ ፡ አመለጠ ። ፲፩ ሳኦልም ፡ ዳዊትን ፡ ጠብቀው ፡ በነጋው ፡ እንዲገድሉት ፡ መልእክተኞቹን ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ቤት ፡ ላከ ፤ ሚስቱም ፡ ሜልኮል ፡— በዚህች ፡ ሌሊት ፡ ነፍስህን ፡ ካላዳንህ ፡ ነገ ፡ ትገደላለህ ፡ ብላ ፡ ነገረችው ። ፲፪ ሜልኮልም ፡ ዳዊትን ፡ በመስኮት ፡ አወረደችው ፤ ሄደም ÷ ሸሽቶም ፡ አመለጠ ። ፲፫ ሜልኮልም ፡ ተራፊምን ፡ ወስዳ ፡ በአልጋ ፡ ላይ ፡ አኖረችው ÷ በራስጌውም ፡ ጕንጕን ፡ የፍየል ፡ ጠጕር ፡ አደረገች ÷ በልብስም ፡ ከደነችው ። ፲፬ ሳኦልም ፡ ዳዊትን ፡ እንዲያመጡት ፡ መልእክተኞችን ፡ ላከ ÷ እርስዋም ፡— ታምሞአል ፡ አለቻቸው ። ፲፭ ሳኦልም ፡— እገድለው ፡ ዘንድ ፡ ዳዊትን ፡ ከነ ፡ አልጋው ፡ አምጡልኝ ፡ ብሎ ፡ መልእክተኞቹን ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ሰደደ ። ፲፮ መልእክተኞቹም ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ እነሆ ÷ ተራፊሙን ፡ በአልጋው ፡ ላይ ፡ አገኙ ÷ በራስጌውም ፡ ጕንጕን ፡ የፍየል ፡ ጠጕር ፡ ነበረ ። ፲፯ ሳኦልም ፡ ሜልኮልን ፡— ስለ ፡ ምን ፡ እንዲህ ፡ አድርገሽ ፡ አታለልሽኝ ? ጠላቴን ፡ አስኰበለልሽው ፡ አላት ። ሜልኮልም ፡ ለሳኦል ፡— እርሱ ፡— አውጥተሽ ፡ ስደጂኝ ÷ አለዚያም ፡ እገድልሻለሁ ፡ አለኝ ፡ ብላ ፡ መለሰችለት ።

፲፰ ዳዊትም ፡ ሸሽቶ ፡ አመለጠ ÷ ወደ ፡ አርማቴምም ፡ ወደ ፡ ሳሙኤል ፡ መጣ ÷ ሳኦልም ፡ ያደ

ረገበትን ፡ ሁሉ ፡ ነገረው ፤ እርሱና ፡ ሳሙኤ ልም ፡ ሄዱ ፥ በነዋትዘራማም ፡ ተቀመጡ ።
፲፱፤ ሳኦልም ፡— ዳዊት ፥ እነሆ ፥ በአርማቴም ፡ አገር ፡ በነዋትዘራማ ፡ ተቀምጦአል ፡ የሚል ፡ ወሬ ፡
፳፤ ሰማ ። ሳኦልም ፡ ዳዊትን ፡ ያመጡት ፡ ዘንድ ፡ መልእክተኞችን ፡ ሰደደ ፤ የነቢያት ፡ ጉባኤ ፡ ትንቢት ፡ ሲናገሩ ፥ ሳሙኤልም ፡ አለቃቸው ፡ ሆኖ ፡ ሲቆም ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ በሳኦል ፡ መልእክተኞች ፡ ላይ ፡ ወረደ ፥
፳፩፤ እነርሱም ፡ ትንቢት ፡ ይናገሩ ፡ ጀመር ። ሳኦ ልም ፡ ያንን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ሌሎች ፡ መልእክተ ኞችን ፡ ሰደደ ፥ እነርሱም ፡ ደግሞ ፡ ትንቢት ፡ ተናገሩ ። ሳኦልም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ሦስተኛ ፡ ጊዜ ፡ መልእክተኞችን ፡ ሰደደ ፥ እነርሱም ፡ ደግሞ ፡
፳፪፤ ትንቢት ፡ ተናገሩ ። የሳኦልም ፡ ቍጣ ፡ ነደደ ፥ እርሱም ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ አርማቴም ፡ መጣ ፥ በሤኩም ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ ታላቁ ፡ የውኃ ፡ ጕድ ጓድ ፡ ደረሰ ። ሳሙኤልና ፡ ዳዊት ፡ የት ፡ ናቸው ? ብሎ ፡ ጠየቀ ፤ አንድ ፡ ሰውም ፡— እነሆ ፥ በአ ርማቴም ፡ አገር ፡ በነዋትዘራማ ፡ ናቸው ፡ አለው ።
፳፫፤ ወደ ፡ አርማቴምም ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ነዋትዘራማ ፡ ሄደ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በእርሱ ፡ ደግሞ ፡ ወረደ ፥ እርሱም ፡ ሄደ ፥ ወደ ፡ አርማ ቴምም ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ነዋትዘራማ ፡ እስኪመጣ ፡
፳፬፤ ድረስ ፡ ትንቢት ፡ ይናገር ፡ ነበር ። ልብሱንም ፡ አወለቀ ፥ በሳሙኤልም ፡ ፊት ፡ ትንቢት ፡ ተና ገረ ፥ ራቁቱንም ፡ ወድቆ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ሁሉ ፡ በዚያም ፡ ሌሊት ፡ ሁሉ ፡ ተጋደመ ። ስለዚህ ፡— ሳኦል ፡ ደግሞ ፡ ከነቢያት ፡ መካከል ፡ ነውን ? ይባባሉ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩፤ ዳዊትም ፡ ከአርማቴም ፡ አገር ፡ ከነዋትዘራማ ፡ ሸሸ ፥ ወደ ፡ ዮናታንም ፡ መጥቶ ፡— ምን ፡ አደ ረግሁ ? እኔንስ ፡ ለመግደል ፡ የሚፈልግ ፡ በአ ባትህ ፡ ፊት ፡ ጠማምነቴና ፡ ኃጢአቴ ፡ ምን
፪፤ ድር ፡ ነው ? ብሎ ፡ ተናገረው ። ዮናታንም ፡— ይህንስ ፡ ያርቀው ፥ አትሞትም ፤ እነሆ ፥ አባቴ ፡ አስቀድሞ ፡ ለእኔ ፡ ሳይገልጥ ፡ ትልቅም ፡ ትን ሽም ፡ ነገር ፡ ቢሆን ፡ አያደርግም ፤ አባቴስ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ለምን ፡ ይሰውረኛል ? እንዲህ ፡
፫፤ አይደለም ፡ አለው ። ዳዊትም ፡— እኔ ፡ በፊ ትህ ፡ ሞገስ ፡ እንዳገኘሁ ፡ አባትህ ፡ በእውነት ፡ ያውቃል ፤ እርሱም ፡— ዮናታን ፡ እንዳይከፋው ፡ አይወቅ ፡ ይላል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሕያው ፡ እግዚአ ብሔርን ! በሕያው ፡ ነፍስህም ፡ እምላለሁ ! በእ ኔና ፡ በሞት ፡ መካከል ፡ አንድ ፡ እርምጃ ፡ ያህል ፡
፬፤ ቀርቶአል ፡ ብሎ ፡ ማለ ። ዮናታንም ፡ ዳዊ ትን ፡— ነፍስህ ፡ የወደደችውን ፡ ሁሉ ፡ አደር
፭፤ ግልሃለሁ ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ ዮናታንን ፡ አለው ፡— እነሆ ፥ ነገ ፡ መባቻ ፡ ነው ፤ በንጉ ሥም ፡ አጠገብ ፡ ለምሳ ፡ አልቀመጥም ፤ እስከ ፡ ሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ በውጭ ፡
፮፤ በሜዳ ፡ እንድሸሸግ ፡ አሰናብተኝ ። አባትህም ፡ ቢፈልገኝ ፡— ለዘመዶቹ ፡ ሁሉ ፡ በዚያ ፡ በቤተ ፡ ልሔም ፡ የዓመት ፡ መሥዋዕት ፡ አላቸውና ፡ ዳዊት ፡ ወደ ፡ ከተማው ፡ ፈጥኖ ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡
፯፤ አጽንቶ ፡ ለምኖኛል ፡ በለው ። እርሱም ፡— መል ካም ፡ ነው ፡ ቢል ፡ ለእኔ ፡ ለባሪያህ ፡ ደኅንነት ፡ ይሆናል ፤ ቢቈጣ ፡ ግን ፡ ክፉት ፡ ከእርሱ ፡ ዘንድ ፡
፰፤ በእኔ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተቈረጠች ፡ እወቅ ። እን ግዲህ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ከባሪ ያህ ፡ ጋር ፡ አድርገሃልና ፡ ለባሪያህ ፡ ቸርነት ፡ አድርግ ፤ በደል ፡ ግን ፡ ቢገኝብኝ ፡ አንተ ፡ ግደ ለኝ ፤ ለምን ፡ ወደ ፡ አባትህ ፡ ታደርሰኛለህ ?
፱፤ ዮናታንም ፡— ይህ ፡ ከአንተ ፡ ይራቅ ፤ ከአባቴ ፡ ዘንድ ፡ ክፉት ፡ በላይህ ፡ እንደ ፡ ተቈረጠች ፡ ያወቅሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አልነግርህምን ? አለ ።
፲፤ ዳዊትም ፡ ዮናታንን ፡— አባትህ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ የነገረህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ማን ፡ ይነግረ
፲፩፤ ኛል ? አለው ። ዮናታንም ፡ ዳዊትን ፡— ና ፥ ወደ ፡ ሜዳ ፡ እንውጣ ፡ አለው ። ሁለቱም ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡ ወጡ ።
፲፪፤ ዮናታንም ፡ ዳዊትን ፡ አለው ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምስክር ፡ ይሁን ፤ ነገ ፡ ወይም ፡ ከነገ ፡ ወዲያ ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ አባቴን ፡ መርምሬ ፥ እነሆ ፥ በዳዊት ፡ ላይ ፡ መልካም ፡
፲፫፤ ቢያስብ ፡ ልኬ ፡ እገልጥልሃለሁ ፤ አባቴም ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ክፉት ፡ ማድረግ ፡ ቢወድድ ፡ እኔም ፡ ባላስታውቅህ ፡ በደህና ፡ ትሄድ ፡ ዘንድ ፡ ባላሰናብትህ ፥ እግዚአብሔር ፡ በዮናታን ፡ ይህን ፡ ያድርግ ፡ ይህንም ፡ ይጨምር ፤ እግዚ አብሔርም ፡ ከአባቴ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ከአ
፲፬፤ ንተ ፡ ጋር ፡ ይሁን ። እኔም ፡ እንዳልሞት ፡ በሕይወቴ ፡ ዘመን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቸርነት ፡
፲፭፤ አድርግልኝ ፤ ደግሞም ፡ እግዚአብሔር ፡ የዳ ዊትን ፡ ጠላቶች ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ ከምድር ፡ በጠፋቸው ፡ ጊዜ ፡ ለዘላለም ፡ ቸርነትህን ፡ ከቤቴ ፡
፲፮፤ አታርቀው ። ዮናታንም ፡— እግዚአብሔር ፡ ከዳዊት ፡ ጠላቶች ፡ እጅ ፡ ይፈልገው ፡ ብሎ ፡ ከዳዊት ፡ ቤት ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረገ ።
፲፯፤ ዮናታንም ፡ ዳዊትን ፡ እንደ ፡ ነፍሱ ፡ ይወድድ ፡ ነበርና ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ማለለት ።
፲፰፤ ዮናታንም ፡ አለው ፡— ነገ ፡ መባቻ ፡ ነው ፥ መቀ መጫህም ፡ ባዶ ፡ ሆኖ ፡ ይገኛልና ፡ ትታሰባለህ ።
፲፱፤ ሦስት ፡ ቀንም ፡ ያህል ፡ ቆይ ፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ፈጥነህ ፡ ውረድ ፥ ነገሩም ፡ በተደረገበት ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ተሸሸግህበት ፡ ስፍራ ፡ ሂድ ፥ በኤዜል ፡
፳፤ ድንጋይም ፡ አጠገብ ፡ ቆይ ። እኔም ፡ በዓላማ ፡ ላይ ፡ እወረውራለሁ ፡ ብዬ ፡ ሦስት ፡ ፍላጻዎችን ፡
፳፩፤ ወደ ፡ አጠገቡ ፡ እወረውራለሁ ። እነሆም ፡— ሂድ ፡ ፍላጻዎችን ፡ ፈልግ ፡ ብዬ ፡ ብላቴናውን ፡ እልክዋለሁ ፤ ብላቴናውንም ፡— እነሆ ፥ ፍላ ጻው ፡ ከአንተ ፡ ወዲህ ፡ ነው ፤ ይዘኸው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ና ፡ ያልሁት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! ለአንተ ፡ ደኅንነት ፡ ነውና ፡
፳፪፤ ምንም ፡ የለብህም ። ብላቴናውን ፡ ግን ፡— እነሆ ፥ ፍላጻው ፡ ከአንተ ፡ ወዲያ ፡ ነው ፡ ያል

ሁት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ እግዚአብሔር ፡ አሰናብቶሃ
፳፫ ልና ፡ መንገድህን ፡ ሂድ ። አንተና ፡ እኔም ፡
ስለ ፡ ተነጋገርነው ፥ እነሆ ፥ እግዚአብሔር ፡ ለዘ
ላለም ፡ በመካከላችን ፡ ምስክር ፡ ነው ።

፳፬ ዳዊትም ፡ በሜዳው ፡ ተሸሸገ ፤ መባቻም ፡
በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሡ ፡ ግብር ፡ ለመብላት ፡ ተቀ
፳፭ መጠ ። ንጉሡም ፡ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ በግ
ንቡ ፡ አጠገብ ፡ በዙፋኑ ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ፤ ዮና
ታንም ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፥ አበኔርም ፡ በሳኦል ፡ አጠ
ገብ ፡ ተቀመጠ ፤ የዳዊትም ፡ ስፍራ ፡ በዶውን ፡
፳፮ ነበረ ። ሳኦልም ፡— አንድ ፡ ነገር ፡ ሆኖአል ፥
ንጹሕም ፡ አይደለም ፤ በእውነት ፡ ንጹሕ ፡
አይደለም ፡ ብሎ ፡ አስቦአልና ፡ በዚያን ፡ ቀን ፡
፳፯ ምንም ፡ አልተናገረም ። ከመባቻም ፡ በኋላ ፡
በማግሥቱ ፡ በሁለተኛው ፡ ቀን ፡ የዳዊት ፡ ስፍራ ፡
በዶውን ፡ ነበረ ፤ ሳኦልም ፡ ልጁን ፡ ዮናታንን ፡—
የእሴይ ፡ ልጅ ፡ ትናንትና ፡ ወይም ፡ ዛሬ ፡ ግብር ፡
ሊበላ ፡ ያልመጣ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ነው ? አለው ።
፳፰ ዮናታንም ፡ ለሳኦል ፡— ዳዊት ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡
ልሔም ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ አጽንቶ ፡ ለመነኝ ፤
፳፱ እርሱም ፡— ዘመዶቼ ፡ በከተማ ፡ ውስጥ ፡ መሥ
ዋዕት ፡ አላቸውና ፥ ወንድሜም ፡ ጠርቶኛልና ፡
እባክህ ፥ አሰናብተኝ ፤ አሁንም ፡ በዓይኖችህ ፡
ሞገስ ፡ አግኝቼ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ልሂድና ፡ ወን
ድሞቼን ፡ ልይ ፡ አለ ፤ ስለዚህ ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡
ሰደቃ ፡ አልመጣም ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።

፴ የሳኦልም ፡ ቍጣ ፡ በዮናታን ፡ ላይ ፡ ነደደና ፡—
አንተ ፡ የጠማማ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፥ የእሴይን ፡
ልጅ ፡ ለአንተ ፡ ማፈርያ ፡ ለእናትህም ፡ ኀፍረተ ፡
ሥጋ ፡ ማፈርያ ፡ እንደ ፡ መረጥህ ፡ እኔ ፡ አላው
፴፩ ቅምን ? የእሴይም ፡ ልጅ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በሕ
ይወት ፡ በሚኖርበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ አንተና ፡
መንግሥትህ ፡ አትጸኑም ፤ አሁንም ፡ የሞት ፡
ልጅ ፡ ነውና ፡ ልከህ ፡ አስመጣልኝ ፡ አለው ።
፴፪ ዮናታንም ፡ ለአባቱ ፡ ለሳኦል ፡— ስለ ፡ ምን ፡
ይሞታል ? ያደረገውስ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብሎ ፡
፴፫ መለሰለት ። ሳኦልም ፡ ሊወጋው ፡ ጦሩን ፡ ወረ
ወረበት ፤ ዮናታንም ፡ አባቱ ፡ ዳዊትን ፡ ፈጽሞ ፡
፴፬ ሊገድለው ፡ እንደ ፡ ፈቀደ ፡ አወቀ ። አባቱ ፡
ዳዊትን ፡ ስላሳፈረው ፡ ዮናታን ፡ ስለ ፡ ዳዊት ፡
አዝኖአልና ፡ እጅግ ፡ ተቈጥቶ ፡ ከሰደቃው ፡
ተነሣ ፥ በመባቻውም ፡ በሁለተኛ ፡ ቀን ፡ ግብር ፡
አልበላም ።

፴፭ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በነጋው ፡ ዮናታን ፡ ከዳዊት ፡
ጋር ፡ ወደ ፡ ተቃጠረበት ፡ ቦታ ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡
ወጣ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ታናሽ ፡ ብላቴና ፡
፴፮ ነበረ ። ብላቴናውንም ፡— ሮጠህ ፡ የምወረው
ራቸውን ፡ ፍላጻዎች ፡ ፈልግልኝ ፡ አለው ።
ብላቴናውም ፡ በሮጠ ፡ ጊዜ ፡ ፍላጻውን ፡ ወደ ፡
፴፯ ማዶ ፡ ወረወረው ። ብላቴናውም ፡ ዮናታን ፡
ፍላጻውን ፡ ወደ ፡ ወረወረበት ፡ ስፍራ ፡ በመጣ ፡
ጊዜ ፡ ዮናታን ፡— ፍላጻው ፡ ከአንተ ፡ ወዲያ ፡
፴፰ ነው ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ብላቴናው ፡ ጮኸ ። ዮና
ታንም ፡ ደግሞ ፡— ቶሎ ፡ ፍጠን ፥ አትቆይ ፡
ብሎ ፡ ወደ ፡ ብላቴናው ፡ ጮኸ ፤ የዮናታንም ፡
ብላቴና ፡ ፍላጻዎቹን ፡ ሰብስቦ ፡ ወደ ፡ ጌታው ፡
፴፱ መጣ ። ዮናታንና ፡ ዳዊት ፡ ብቻ ፡ ነገሩን ፡
ያውቁ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ብላቴናው ፡ ምንም ፡
፵ አያውቅም ፡ ነበር ። ዮናታንም ፡ መሣርያውን ፡
ለብላቴናው ፡ ሰጥቶ ፡— ወደ ፡ ከተማ ፡ ውሰድ ፡
፵፩ አለው ። ብላቴናውም ፡ በሄደ ፡ ጊዜ ፡ ዳዊት ፡
ከስፍራው ፡ በደቡብ ፡ አጠገብ ፡ ተነሣ ፥ በምድ
ርም ፡ ላይ ፡ በግምባሩ ፡ ተደፋ ፥ ሦስት ፡ ጊዜም ፡
ለሰላምታ ፡ ሰገደ ፤ እየተላቀሱም ፡ እርስ ፡ በእ
ርሳቸው ፡ ተሳሳሙ ፥ ይልቁንም ፡ ዳዊት ፡ እጅግ ፡
፵፪ አለቀሰ ። ዮናታንም ፡ ዳዊትን ፡— በደኅና ፡
ሂድ ፤ እነሆ ፥ እኛ ፡ ሁለታችን ፡ በእኔና ፡ በአ
ንተ ፥ በዘሬና ፡ በዘርህ ፡ መካከል ፡ ለዘላለም ፡
እግዚአብሔር ፡ ይሁን ፡ ብለን ፡ በእግዚአብሔር ፡
ስም ፡ ተማምለናል ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ ተነ
ሥቶ ፡ ሄደ ፤ ዮናታንም ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ገባ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ወደ ፡ አቢሜሌክ ፡
ወደ ፡ ኖብ ፡ መጣ ፤ አቢሜሌክም ፡ እየተንቀጠ
ቀጠ ፡ ዳዊትን ፡ ሊገናኘው ፡ መጣና ፡— ስለ ፡
ምን ፡ አንተ ፡ ብቻህን ፡ ነህ ? ከአንተስ ፡ ጋር ፡
፪ ስለ ፡ ምን ፡ ማንም ፡ የለም ? አለው ። ዳዊትም ፡
ካህኑን ፡ አቢሜሌክን ፡— የተላክህበትን ፡ ነገ
ርና ፡ የሰጠሁህን ፡ ትእዛዝ ፡ ማንም ፡ አይወቅ ፡
ብሎ ፡ ንጉሡ ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ አዝዞኛል ፤ ስለዚ
ህም ፡ ብላቴኖቹን ፡ እንዲህ ፡ በለ ፡ ስፍራ ፡ ተው
፫ ኋቸው ። አሁንስ ፡ በእጅህ ፡ ምን ፡ አለ ? አም
ስት ፡ እንጀራ ፡ ወይም ፡ የተገኘውን ፡ በእጄ ፡
፬ ስጠኝ ፡ አለው ። ካህኑም ፡ ለዳዊት ፡ መልሶ ፡—
ሁሉ ፡ የሚበላው ፡ እንጀራ ፡ የለኝም ፥ ነገር ፡
ግን ፡ የተቀደሰ ፡ እንጀራ ፡ አለ ፤ ብላቴኖቹ ፡ ከሴ
ቶቹ ፡ ንጹሐን ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ መብላት ፡ ይቻ
፭ ላል ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ ለካህኑ ፡ መልሶ ፡—
በእውነት ፡ ከወጣን ፡ ጀምረን ፡ እኛ ፡ ሰውነታ
ችንን ፡ ከሴቶች ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ጠብቀናል ፤
የብላቴኖችም ፡ ዕቃ ፡ የተቀደሰች ፡ ናት ፤ ስለ
ዚህ ፡ ዛሬ ፡ ዕቃቸው ፡ የተቀደሰች ፡ በመሆንዋ ፡
እንጀራው ፡ እንደሚበላ ፡ እንጀራ ፡ ይሆናል ፡
፮ አለው ። ካህኑም ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ትኩስ ፡
እንጀራ ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ከተነሣው ፡ ከገጹ ፡ ኅብስት ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡
እንጀራ ፡ አልነበረምና ፡ የተቀደሰውን ፡ እን
ጀራ ፡ ሰጠው ።

፯ በዚያም ፡ ቀን ፡ ከሳኦል ፡ ባሪያዎች ፡ አንድ ፡
ሰው ፡ በዚያ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ተገኝቶ ፡
ነበር ፤ ስሙም ፡ ኤዶማዊው ፡ ዶይቅ ፡ ነበረ ፥
፰ ለሳኦልም ፡ የእረኞቹ ፡ አለቃ ፡ ነበረ ። ዳዊትም ፡
አቢሜሌክን ፡— የንጉሥ ፡ ጉዳይ ፡ ስላስቸኰ
ለኝ ፡ ሰይፌንና ፡ መሣርያዬን ፡ አላመጣሁምና ፡
በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ጦር ፡ ወይም ፡ ሰይፍ ፡ አለ ፡
፱ ወይ ? አለው ። ካህኑም ፡— በኤላ ፡ ሸለቆ ፡ የገደ
ልኸው ፡ የፍልስጥኤማዊው ፡ የጎልያድ ፡ ሰይፍ ፥

እነሆ ፥ በመጐናጸፊያ ፡ ተጠቅልሎ ፡ ከዚህ ፡ ከኤፉዱ ፡ በኋላ ፡ አለ ፤ ትወድደውም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ውሰደው ፤ ሌላ ፡ ከዚህ ፡ የለም ፡ አለ ። ዳዊትም ፡— እንደ ፡ እርሱ ፡ ያለ ፡ የለምና ፡ እር ሱን ፡ ስጠኝ ፡ አለው ።

፲ ዳዊትም ፡ ተነሣ ፡ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሳኦልን ፡ ፈርቶ ፡ ሸሸ ፥ ወደ ፡ ጌትም ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ አን ኩስ ፡ ሄደ ። ፲፩ የአንኩስ ፡ ባሪያዎችም ፡— ይህ ፡ ዳዊት ፡ የአገሩ ፡ ንጉሥ ፡ አይደለምን ? ሳኦል ፡ ሺህ ፥ ዳዊትም ፡ እልፍ ፡ ገደለ ፡ ብለው ፡ ሴቶች ፡ በዘፈን ፡ የዘመሩለት ፡ እርሱ ፡ አይደለምን ? አሉት ። ፲፪ ዳዊትም ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ በልቡ ፡ አኖረ ፥ የጌትንም ፡ ንጉሥ ፡ አንኩስን ፡ እጅግ ፡ ፈራ ። ፲፫ በፊታቸውም ፡ አእምሮውን ፡ ለወጠ ፥ በያዙትም ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ እብድ ፡ ሆነ ፤ በበ ሩም ፡ መድረክ ፡ ላይ ፡ ተንፈራፈረ ፥ ልጋጉም ፡ በጢሙ ፡ ላይ ፡ ይወርድ ፡ ነበር ። ፲፬ አንኩስም ፡ ባሪያዎቹን ፡— እነሆ ፥ ይህ ፡ ሰው ፡ እብድ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አይታችኋል ፤ ለምን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አመጣችሁት ? ፲፭ በፊቴ ፡ ያብድ ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡ ያመጣችሁት ፡ እብድ ፡ ጠፍቶብኝ ፡ ነውን ? እን ዲህ ፡ ያለውስ ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ ይገባልን ? አላ ቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ ዳዊትም ፡ ከዚያ ፡ ተነሣ ፡ ወደ ፡ ዓዶላም ፡ ዋሻ ፡ ኰበለለ ፤ ወንድሞቹና ፡ የአባቱ ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፡ ሁሉ ፡ ይህን ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ፪ ወደዚያ ፡ ወረዱ ። የተጨነቀም ፡ ሁሉ ፥ ብድ ርም ፡ ያለበት ፡ ሁሉ ፥ የተከፋም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተከማቹ ፤ እርሱም ፡ በላያቸው ፡ አለቃ ፡ ሆነ ፤ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ አራት ፡ መቶ ፡ የሚያህሉ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ።

፫ ዳዊትም ፡ ከዚያ ፡ በሞዓብ ፡ ምድር ፡ ወዳለ ችው ፡ ወደ ፡ ምጽጳ ፡ ሄደ ፤ የሞዓብንም ፡ ንጉሥ ፡— እግዚአብሔር ፡ የሚያደርግልኝን ፡ እስካውቅ ፡ ድረስ ፡ አባቴና ፡ እናቴ ፡ ከእንተ ፡ ጋር ፡ ይቀመጡ ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለው ። ፬ በሞዓብም ፡ ንጉሥ ፡ ፊት ፡ አመጣቸው ፤ ዳዊ ትም ፡ በአምባ ፡ ውስጥ ፡ በነበረበት ፡ ወራት ፡ ፭ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ተቀመጡ ። ነቢዩ ፡ ጋድም ፡ ዳዊትን ፡— ተነሥተህ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ምድር ፡ ሂድ ፡ እንጂ ፡ በአምባው ፡ ውስጥ ፡ አት ቀመጥ ፡ አለው ፤ ዳዊትም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ሔሬት ፡ ዱር ፡ መጣ ።

፮ ሳኦልም ፡ ዳዊትና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ እንደ ፡ ተገለጡ ፡ ሰማ ። ሳኦልም ፡ በጊብዓ ፡ በአ ጣጥ ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ በኮረብታው ፡ ላይ ፡ ተቀ ምጦ ፡ በእጁም ፡ ጦር ፡ ይዞ ፡ ነበር ፤ ባሪያዎቹም ፡ ፯ ሁሉ ፡ በአጠገቡ ፡ ቆመው ፡ ነበር ። ሳኦልም ፡ በአጠገቡ ፡ የቆሙትን ፡ ባሪያዎቹን ፡— ብንያማ ውያን ፡ ሆይ ፥ እንግዲህ ፡ ስሙ ፤ በውኑ ፡ የእ ሴይ ፡ ልጅ ፡ እርሻና ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ ለሁላችሁ ፡ ይሰጣችኋልን ? ሁላችሁንስ ፡ ሻለቆችና ፡ የመቶ ፡ አለቆች ፡ ያደርጋችኋልን ? ፰ ሁላችሁ ፡ በላዬ ፡ ዶልታችሁ ፡ ተነሣችሁብኝ ፤ ልጄ ፡ ከእሴይ ፡ ልጅ ፡ ጋር ፡ ሲማማል ፡ ማንም ፡ አይገልጥልኝም ፥ ከእናንተም ፡ አንድ ፡ ለእኔ ፡ የሚያዝን ፡ የለም ፥ ዛሬም ፡ እንደ ፡ ሆነው ፡ ሁሉ ፡ ልጄ ፡ ባሪያዬን ፡ እንዲዶልት ፡ ሲያስነሣብኝ ፡ ማንም ፡ አላስታወ ቀኝም ፡ አላቸው ። ፱ በሳኦልም ፡ ባሪያዎች ፡ አጠ ገብ ፡ የቆመው ፡ ኤዶማዊው ፡ ዶይቅ ፡ መልሶ ፡— የእሴይ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኖብ ፡ ወደ ፡ አኪጦብ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ አቢሜሌክ ፡ ሲመጣ ፡ አይቼዋለሁ ። ፲ እግ ዚአብሔርንም ፡ ጠየቀለት ፥ ስንቅንም ፡ ሰጠው ፥ የፍልስጥኤማዊውንም ፡ የጎልያድን ፡ ሰይፍ ፡ ሰጠው ፡ አለ ።

፲፩ ንጉሡም ፡ የአኪጦብን ፡ ልጅ ፡ ካህኑን ፡ አቢ ሜሌክን ፡ በኖብም ፡ ያሉትን ፡ ካህናት ፡ የአባ ቱን ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ልኮ ፡ አስጠራቸው ፤ ሁላቸ ውም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ መጡ ። ፲፪ ሳኦልም ፡— የአ ኪጦብ ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ እንግዲህ ፡ ስማ ፡ አለ ፤ እርሱም ፡— እነሆኝ ፥ ጌታዬ ፡ ሆይ ፡ ብሎ ፡ መለሰ ። ፲፫ ሳኦልም ፡— አንተና ፡ የእሴይ ፡ ልጅ ፡ ለምን ፡ ዶለታችሁብኝ ? እንጀራና ፡ ሰይፍ ፡ ሰጠኸው ፥ ዛሬም ፡ እንደ ፡ ተደረገው ፡ ጠላት ፡ ሆኖ ፡ ይነሣብኝ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ጠየቅህለት ፡ አለው ። ፲፬ አቢሜሌክም ፡ መልሶ ፡ ንጉሡን ፡— ከባሪያዎችህ ፡ ሁሉ ፡ የታ መነ ፥ ለንጉሥም ፡ አማች ፡ የሆነ ፥ በትእዛዝህ ፡ የሚሄድ ፥ በቤትህም ፡ የከበረ ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፡ ያለ ፡ ማን ፡ ነው ? ፲፭ በውኑ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ እግዚ አብሔርን ፡ እጠይቅ ፡ ዘንድ ፡ ዛሬ ፡ ጀመርሁን ? ይህ ፡ ከእኔ ፡ ይራቅ ፤ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ እጅግ ፡ ወይም ፡ ጥቂት ፡ ቢሆን ፡ አላውቅምና ፡ ንጉሡ ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ በእኔ ፡ በባ ሪያውና ፡ በአባቴ ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አያኑር ፡ አለ ። ፲፮ ንጉሡም ፡— አቢሜሌክ ፡ ሆይ ፥ አን ተና ፡ የአባትህ ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ፈጽማችሁ ፡ ትሞ ታላችሁ ፡ አለ ። ፲፯ ንጉሡም ፡ በዙሪያው ፡ የቆሙ ትን ፡ እግረኞች ፡— የእግዚአብሔር ፡ ካህናት ፡ እጅ ፡ ከዳዊት ፡ ጋር ፡ ነውና ፥ ኰብለላውንም ፡ ሲያውቁ ፡ በጆሮዬ ፡ አልገለጡምና ፡ ዞራችሁ ፡ ግደሉአቸው ፡ አላቸው ። የንጉሡ ፡ ባሪያዎች ፡ ግን ፡ እጃቸውን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ካህናት ፡ ላይ ፡ ይዘረጉ ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ አሉ ። ፲፰ ንጉሡም ፡ ዶይቅን ፡— አንተ ፡ ዞረህ ፡ በካህናቱ ፡ ላይ ፡ ውደ ቅባቸው ፡ አለው ። ኤዶማዊውም ፡ ዶይቅ ፡ ዞሮ ፡ በካህናቱ ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፥ በዚያም ፡ ቀን ፡ የበፍታ ፡ ኤፉድ ፡ የለበሱትን ፡ ሰማንያ ፡ አም ስት ፡ ሰዎች ፡ ገደለ ። ፲፱ የካህናቱንም ፡ ከተማ ፡ ኖብን ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ መታ ፤ ወንዶችንና ፡ ሴቶችንም ፥ ብላቴኖችንና ፡ ጡት ፡ የሚጠቡ ትን ፥ በሬዎችንና ፡ አህዮችንም ፡ በጎችንም ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ ገደለ ።

፳ ከአኪጦብም ፡ ልጅ ፡ ከአቢሜሌክ ፡ ልጆች ፡ ስሙ ፡ አብያታር ፡ የሚባል ፡ አንዱ ፡ ልጅ ፡ አም ልጦ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ሸሸ ። ፳፩ አብያታርም ፡ ሳኦል ፡

የእግዚአብሔርን ፡ ካህናት ፡ እንደ ፡ ፈጀ ፡ ለዳ
፳፪ ዊት ፡ ነገረው ። ዳዊት ፡ አብያታርን ፦ ኤዶማ
ዊው ፡ ዶይቅ ፡ በዚያ ፡ መኖሩን ፡ በየሁ ፡ ጊዜ ፦
ለሳኦል ፡ በእርግጥ ፡ ይነግራል ፡ ብዬ ፡ በዚያው ፡
ቀን ፡ አውቄዋለሁ ፤ ለአባትህ ፡ ቤት ፡ ነፍስ ፡
ሁሉ ፡ የጥፋታቸው ፡ ምክንያት ፡ እኔ ፡ ነኝ ።
፳፫ ነፍሴን ፡ የሚፈልግ ፡ የአንተን ፡ ነፍስ ፡ ይፈል
ጋልና ÷ ከእኔም ፡ ጋር ፡ ተጠብቀህ ፡ ትኖራለ
ህና ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ተቀመጥ ÷ አትፍራ ፡ አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ ለዳዊትም ፦ እነሆ ÷ ፍልስጥኤማውያን ፡
ቅዒላን ፡ ይወጋሉ ÷ አውድማውንም ፡ ይዘር
፪ ፉሉ ፡ የሚል ፡ ወሬ ፡ ደረሰው ። ዳዊትም ፦
ልሂድን ? እነዚህንስ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ልም
ታን ? ብሎ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠየቀ ፤ እግዚ
አብሔርም ፡ ዳዊትን ፦ ሂድ ÷ ፍልስጥኤማው
፫ ያንን ፡ ምታ ፡ ቅዒላንም ፡ አድን ፡ አለው ። የዳ
ዊትም ፡ ሰዎች ፦ እነሆ ÷ በዚህ ፡ በይሁዳ ፡
መቀመጥ ፡ እንፈራለን ÷ ይልቁንስ ፡ በፍልስጥ
ኤማውያን ፡ ጭፍሮች ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ቅዒላ ፡ ብን
፬ ሄድ ፡ እንዴት ፡ ነው ? አሉት ። ዳዊትም ፡ ደግሞ ፡
እግዚአብሔርን ፡ ጠየቀ ፤ እግዚአብሔርም ፡
መለሰ ፦ ፍልስጥኤማውያንን ፡ በእጅህ ፡ አሳ
ልፌ ፡ እሰጣለሁና ፡ ተነሥተህ ፡ ወደ ፡ ቅዒላ ፡
፭ ውረድ ፡ አለው ። ዳዊትና ፡ ሰዎቹም ፡ ወደ ፡
ቅዒላ ፡ ሄዱ ÷ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ ጋር ፡
ተዋጉ ፤ እንስሶቻቸውንም ፡ ማረኩ ÷ በታላ
ቅም ፡ አገዳደል ፡ ገደሉአቸው ። ዳዊትም ፡ በቅ
ዒላ ፡ የሚኖሩትን ፡ አዳነ ።
፮ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ የአቢሜሌክ ፡ ልጅ ፡ አብ
ያታር ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ወደ ፡ ቅዒላ ፡ በኰበለለ ፡
፯ ጊዜ ፡ ኤፉዱን ፡ ይዞ ፡ ወርዶ ፡ ነበር ። ሳኦልም ፡
ዳዊት ፡ ወደ ፡ ቅዒላ ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ ሰማ ፤ ሳኦ
ልም ፦ መዝጊያና ፡ መወርወሪያ ፡ ወዳለበት ፡
ከተማ ፡ ገብቶ ፡ ተገኝቶአልና ፡ እግዚአብሔር ፡
፰ በእጄ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶታል ፡ አለ ። ሳኦልም ፡
ወደ ፡ ቅዒላ ፡ ወርደው ፡ ይዋጉ ፡ ዘንድ ÷ ዳዊት
ንና ፡ ሰዎቹንም ፡ ይከብቡ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝቡን ፡
፱ ሁሉ ፡ አዘዘ ። ዳዊትም ፡ ሳኦል ፡ ክፉን ፡ እንዳ
ሰበበት ፡ አወቀ ፤ ካህኑን ፡ አብያታርንም ፦
፲ ኤፉዱን ፡ ወደዚህ ፡ አምጣ ፡ አለው ። ዳዊትም ፦
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ÷ በእኔ ፡ ምክን
ያት ፡ ከተማይቱን ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ ሳኦል ፡ ወደ ፡
ቅዒላ ፡ ሊመጣ ፡ እንደሚፈልግ ፡ እኔ ፡ ባሪያህ ፡
፲፩ ፈጽሜ ፡ ሰምቻለሁ ። የቅዒላ ፡ ሰዎች ፡ በእጁ ፡
አሳልፈው ፡ ይሰጡኛልን ? ባሪያህስ ፡ እንደ ፡
ሰማ ፡ ሳኦል ፡ በውኑ ፡ ይወርዳልን ? የእስራኤል ፡
አምላክ ፡ አቤቱ ÷ እንድትነግረኝ ፡ እለምንሃ
ለሁ ፡ አለ ። እግዚአብሔርም ፦ ይወርዳል ፡
፲፪ አለ ። ዳዊትም ፦ የቅዒላ ፡ ሰዎች ፡ እኔንና ፡
ሰዎቼን ፡ በሳኦል ፡ እጅ ፡ አሳልፈው ፡ ይሰጡና
ልን ? አለ ። እግዚአብሔርም ፦ አሳልፈው ፡
፲፫ ይሰጡአችኋል ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ። ዳዊትና ፡ ስድ
ስት ፡ መቶ ፡ የሚሆኑ ፡ ሰዎችም ፡ ተነሥተው ፡
ከቅዒላ ፡ ወጡ ÷ መሄድም ፡ ወደሚችሉበት ፡
ሄዱ ። ሳኦልም ፡ ዳዊት ፡ ከቅዒላ ፡ እንደ ፡ ሸሸ ፡
ሰማ ፤ ስለዚህም ፡ ከመውጣት ፡ ቀረ ።
፲፬ ዳዊትም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ በአምባ ፡ ውስጥ ፡
ይኖር ፡ ነበር ÷ ከዚፍ ፡ ምድረ ፡ በዳም ፡ ባለው ፡
በተራራማው ፡ አገር ፡ ተቀመጠ ፤ ሳኦልም ፡
ሁልጊዜ ፡ ይፈልገው ፡ ነበር ÷ እግዚአብሔር ፡
፲፭ ግን ፡ በእጁ ፡ አሳልፎ ፡ አልሰጠውም ። ዳዊ
ትም ፡ ሳኦል ፡ ነፍሱን ፡ ሊፈልግ ፡ እንደ ፡ ወጣ ፡
አየ ፤ ዳዊትም ፡ በዚፍ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በጥሻው ፡
፲፮ ውስጥ ፡ ይኖር ፡ ነበር ። የሳኦልም ፡ ልጅ ፡ ዮናታን ፡
ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ወደ ፡ ጥሻው ፡ ውስጥ ፡
ሄደ ፤ እጁንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ አጽንቶ ፦
፲፯ የአባቴ ፡ የሳኦል ፡ እጅ ፡ አታገኝህምና ፡ አትፍራ ፤
አንተም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ትሆና
ለህ ÷ እኔም ፡ ከአንተ ፡ በታች ፡ ሁለተኛ ፡ እሆ
ናለሁ ፤ ይህን ፡ ደግሞ ፡ አባቴ ፡ ሳኦል ፡ ያው
፲፰ ቃል ፡ አለው ። ሁለቱም ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረጉ ፤ ዳዊትም ፡ በጥ
ሻው ፡ ውስጥ ፡ ተቀመጠ ÷ ዮናታንም ፡ ወደ ፡
ቤቱ ፡ ሄደ ።
፲፱ የዚፍ ፡ ሰዎችም ፡ ወደ ፡ ሳኦል ፡ ወደ ፡ ጊብዓ ፡
መጥተው ፦ እነሆ ÷ ዳዊት ፡ በየሴሞን ፡ ደቡብ ፡
በኩል ፡ በኤኬላ ፡ ኮረብታ ፡ ላይ ፡ በጥሻ ፡ ውስጥ ፡
ባሉት ፡ አምባዎች ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ ተሸሽጎ ፡
፳ የለምን ? አሁንም ÷ ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ ትወርድ ፡
ዘንድ ፡ ነፍስህ ፡ እንደ ፡ ወደደች ፡ ውረድ ፤ በን
ጉሡም ፡ እጅ ፡ እርሱን ፡ አሳልፎ ፡ ለመስጠት ፡
፳፩ እኛ ፡ አለን ፡ አሉት ። ሳኦልም ፡ አለ ፦ እና
ንተ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ አዝናችኋልና ፡ ከእግዚአብሔር ፡
፳፪ ዘንድ ፡ የተባረካችሁ ፡ ሁኑ ፤ አሁንም ፡ ደግሞ ፡
ሂዱ ፤ እርሱም ፡ እጅግ ፡ ተንኰለኛ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ሰምቻለሁና ፡ አጥብቃችሁ ፡ ፈልጉት ÷ እግ
ሩም ፡ የሚሄድበትን ፡ ስፍራ ፡ እዩና ፡ እወቁ ÷
፳፫ በዚያ ፡ ያየውንም ፡ ሰው ፡ አግኙ ። እርሱ ፡
የሚደበቅበትንና ፡ የሚሸሸግበትን ፡ ስፍራ ፡
እዩና ፡ እወቁ ÷ በእርግጥም ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ተመ
ለሱ ÷ እኔም ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እሄዳለሁ ፤ በም
ድርም ፡ ውስጥ ፡ ቢሸሸግ ፡ በይሁዳ ፡ አእላፋት ፡
ሁሉ ፡ መከከል ፡ እፈልገዋለሁ ።
፳፬ እነዚያም ፡ ተነሥተው ፡ ከሳኦል ፡ በፊት ፡
ወደ ፡ ዚፍ ፡ ሄዱ ፤ ዳዊትና ፡ ሰዎቹ ፡ ግን ፡ በየሴ
ሞን ፡ ደቡብ ፡ በኩል ፡ በዓረባ ፡ በማዖን ፡ ምድረ ፡
፳፭ በዳ ፡ ነበሩ ። ሳኦልና ፡ ሰዎቹም ፡ ሊፈልጉት ፡
ሄዱ ፤ ዳዊትም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ዓለቱ ፡
ወርዶ ፡ በማዖን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ተቀመጠ ፤ ሳኦ
ልም ፡ ያንን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ዳዊትን ፡ በማዖን ፡
፳፮ ምድረ ፡ በዳ ፡ አሳደደው ። ሳኦልም ፡ በተራ
ራው ፡ በአንድ ፡ ወገን ፡ ሄደ ÷ ዳዊትና ፡ ሰዎ
ቹም ፡ በተራራው ፡ በሌላው ፡ ወገን ፡ ሄዱ ።
ሳኦልና ፡ ሰዎቹም ፡ ዳዊትንና ፡ ሰዎቹን ፡ ለመ
ያዝ ፡ ከብበዎቸው ፡ ነበርና ፡ ዳዊት ፡ ከሳኦል ፡
፳፯ ፊት ፡ ያመልጥ ፡ ዘንድ ፡ ፈጠነ ። ወደ ፡ ሳኦልም ፡

መልእክተኛ ፡ መጥቶ ፡— ፍልስጥኤማውያን ፡
አገሩን ፡ ወርረውታልና ፡ ፈጥነህ ፡ ና ፡ አለው ።
፳፰ ሳኦልም ፡ ዳዊትን ፡ ማሳደድ ፡ ትቶ ፡ ተመለሰ ፥
ከፍልስጥኤማውያንም ፡ ጋር ፡ ሊዋጋ ፡ ሄደ ። ስለ
ዚህ ፡ የዚያ ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ የማምለጥ ፡ ዓለት ፡
፳፱ ተባለ ። ዳዊትም ፡ ከዚያ ፡ ወጥቶ ፡ በዓይንጋዲ ፡
አምባዎች ፡ ተቀመጠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ሳኦል ፡ ፍልስጥኤማውያ
ንን ፡ ከማሳደድ ፡ ከተመለሰ ፡ በኋላ ፡— እነሆ ፥
ዳዊት ፡ በዓይንጋዲ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ አለ ፡ የሚል ፡
፪ ወሬ ፡ ደረሰለት ። ሳኦልም ፡ ከእስራኤል ፡ ሁሉ ፡
የተመረጡትን ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ወሰደ ፥
ዳዊትንና ፡ ሰዎቹንም ፡ ለመፈለግ ፡ የበረሀ ፡ ፍየ
፫ ሎች ፡ ወደ ፡ ነበሩባቸው ፡ ዓለቶች ፡ ሄደ ። በመ
ንገድም ፡ አጠገብ ፡ ወዳሉት ፡ የበጎች ፡ ማደሪ
ያዎች ፡ መጣ ፥ በዚያም ፡ ዋሻ ፡ ነበረ ፤ ሳኦልም ፡
ወገቡን ፡ ይሞክር ፡ ዘንድ ፡ ከዚያ ፡ ገባ ፤ ዳዊ
ትና ፡ ሰዎቹም ፡ ከዋሻው ፡ በውስጠኛው ፡ በታ ፡
፬ ተቀምጠው ፡ ነበር ። የዳዊትም ፡ ሰዎች ፡—
እነሆ ፥ ጠላትህን ፡ በእጅህ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጠ
ዋለሁ ፥ በዓይንህም ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝህን ፡ ታደ
ርግበታለህ ፡ ብሎ ፡ እግዚአብሔር ፡ የነገርህ ፡
ቀን ፥ እነሆ ፥ ዛሬ ፡ ነው ፡ አሉት ። ዳዊትም ፡
ተነሥቶ ፡ የሳኦልን ፡ መጐናጸፊያ ፡ ዘርፍ ፡ በቀ
፭ ስታ ፡ ቈረጠ ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤
የሳኦልን ፡ የልብሱን ፡ ዘርፍ ፡ ስለ ፡ ቈረጠ ፡ የዳ
፮ ዊት ፡ ልብ ፡ በኀዘን ፡ ተመታ ። ሰዎቹንም ፡—
እግዚአብሔር ፡ የቀባው ፡ ነውና ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በቀባው ፡ በጌታዬ ፡ ላይ ፡ እንዲህ ፡ ያለ
ውን ፡ ነገር ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ እጄንም ፡ እጥል
በት ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእኔ ፡ ያርቀው ፡
፯ አላቸው ። ዳዊትም ፡ በዚህ ፡ ቃል ፡ ሰዎቹን ፡
ከለከላቸው ፥ በሳኦልም ፡ ላይ ፡ ይነሡ ፡ ዘንድ ፡
አልተዋቸውም ፤ ሳኦልም ፡ ከዋሻው ፡ ተነሥቶ ፡
መንገዱን ፡ ሄደ ።
፰ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ዳዊት ፡ ደግሞ ፡ ተነሣ ፥
ከዋሻውም ፡ ወጣ ፥ ከሳኦልም ፡ በኋላ ፡— ጌታዬ ፡
ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ ብሎ ፡ ጮኸ ፤ ሳኦልም ፡ ወደ ፡
ኋላው ፡ ተመለከተ ፥ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡
፱ ተጐንብሶ ፡ እጅ ፡ ነሣ ። ዳዊትም ፡ ሳኦልን ፡
አለው ፡— እነሆ ፥ ዳዊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ይሻብ
ሃል ፡ የሚሉህን ፡ ሰዎች ፡ ቃል ፡ ለምን ፡ ትሰማ
፲ ለህ ? እነሆ ፥ ዛሬ ፡ በዋሻው ፡ ውስጥ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ በእጄ ፡ አሳልፎ ፡ እንደ ፡ ሰጠህ ፡ ዓይ
ንህ ፡ አይታለች ፤ አንተንም ፡ እንድገድልህ ፡
ሰዎች ፡ ተናገሩኝ ፤ እኔ ፡ ግን ፡— በእግዚአብ
ሔር ፡ የተቀባ ፡ ነውና ፡ እጄን ፡ በጌታዬ ፡ ላይ ፡
፲፩ አልዘረጋም ፡ ብዬ ፡ ራራሁልህ ። ደግሞም ፥
አባቴ ፡ ሆይ ፥ የልብስህ ፡ ዘርፍ ፡ በእጄ ፡ እንዳለ ፡
ተመልከተህ ፡ እወቅ ፤ የልብስህንም ፡ ዘርፍ ፡
በቈረጥሁ ፡ ጊዜ ፡ አልገደልሁህም ፤ ስለዚህም ፡
በእጄ ፡ ክፋትና ፡ በደል ፡ እንደሌለ ፥ አንተም ፡
ነፍሴን ፡ ልትወስድ ፡ ምንም ፡ ብታሳድደኝ ፡ እን
፲፪ ዳልበደልሁህ ፡ ተመልከተህ ፡ እወቅ ። እግዚ
አብሔር ፡ በእኔና ፡ በአንተ ፡ መካከል ፡ ይፍረድ ፥
እግዚአብሔርም ፡ አንተን ፡ ይበቀልልኝ ፤ እጄ ፡
፲፫ ግን ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ አትሆንም ። በጥንት ፡
ምሳሌ ፡— ከኃጢአተኞች ፡ ኃጢአት ፡ ይወ
ጣል ፡ እንደ ፡ ተባለ ፤ እጄ ፡ ግን ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡
፲፬ አትሆንም ። የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ማንን ፡ ለማ
ሳደድ ፡ መጥቶአል ? አንተስ ፡ ማንን ፡ ታሳድዳ
ለህ ? የሞተ ፡ ውሻን ፡ ወይስ ፡ ቁንጫን ፡ ታሳድ
፲፭ ዳለህን ? እንግዲህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዳኛ ፡
ይሁን ፥ በእኔና ፡ በአንተም ፡ መካከል ፡ ይፍ
ረድ ፥ አይቶም ፡ ይምዋገትልኝ ፥ ከእጅህም ፡
ያድነኝ ።
፲፮ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ዳዊት ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ለሳ
ኦል ፡ መናገር ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፥ ሳኦል ፡— ልጄ ፡
ሆይ ፡ ዳዊት ፥ ይህ ፡ ድምፅህ ፡ ነውን ? አለ ፤
ሳኦልም ፡ ድምፁን ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡ አለቀሰ ።
፲፯ ዳዊትን ፡ አለው ፡— እኔ ፡ ክፉ ፡ በመለስሁልህ ፡
ፋንታ ፡ በጎ ፡ መልሰህልኛልና ፡ አንተ ፡ ከእኔ ፡
፲፰ ይልቅ ፡ ጻድቅ ፡ ነህ ። እግዚአብሔርም ፡ በእ
ጅህ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶኝ ፡ ሳለ ፡ አልገደልኸኝ
ምና ፡ ለእኔ ፡ መልካም ፡ እንዳደረግህልኝ ፡
፲፱ አንተ ፡ ዛሬ ፡ አሳየኸኝ ። ጠላቱን ፡ አግኝቶ ፡
በመልካም ፡ መንገድ ፡ ሸኝቶ ፡ የሚሰድድ ፡
ማን ፡ ነው ? ስለዚህ ፡ ለእኔ ፡ ስላደረግኸው ፡
፳ ቸርነት ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመልስልህ ። አሁ
ንም ፥ እነሆ ፥ አንተ ፡ በእርግጥ ፡ ንጉሥ ፡ እንድ
ትሆን ፡ የእስራኤልም ፡ መንግሥት ፡ በእጅህ ፡
፳፩ እንድትጸና ፡ እኔ ፡ አውቃለሁ ። አሁን ፡ እንግ
ዲህ ፡ ከእኔ ፡ በኋላ ፡ ዘሬን ፡ እንዳትቈርጥ ፡ ከአ
ባቴም ፡ ቤት ፡ ስሜን ፡ እንዳታጠፋው ፡ በእግ
፳፪ ዚአብሔር ፡ ማልልኝ ። ዳዊትም ፡ ለሳኦል ፡
ማለለት ፤ ሳኦልም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ፥ ዳዊትና ፡
ሰዎቹም ፡ ወደ ፡ አምባው ፡ ወጡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

፩ ሳሙኤልም ፡ ሞተ ፤ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡
ተሰብስበው ፡ አለቀሱለት ፥ በአርማቴምም ፡
በቤቱ ፡ ቀበሩት ። ዳዊትም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡
ፋራን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወረደ ።
፪ በማዖንም ፡ የተቀመጠ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፥
ከብቱም ፡ በቀርሜሎስ ፡ ነበረ ፤ እጅግም ፡ ታላቅ ፡
ሰው ፡ ነበረ ፥ ለእርሱም ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ በጎ
ችና ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ ፍየሎች ፡ ነበሩት ፤ በቀር
፫ ሜሎስም ፡ በጎቹን ፡ ይሸልት ፡ ነበር ። የሰውዮ
ውም ፡ ስም ፡ ናባል ፥ የሚስቱም ፡ ስም ፡ አቢ
ግያ ፡ ነበረ ፤ የሴቲቱም ፡ አእምሮ ፡ ታላቅ ፥
መልከዋም ፡ የተዋበ ፡ ነበረ ፤ ሰውዮው ፡ ግን ፡
ባለጌ ፡ ነበረ ፥ ግብሩም ፡ ክፉ ፡ ነበረ ፤ ከካሌብም ፡
፬ ወገን ፡ ነበረ ። ዳዊትም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ሳለ ፡—
ናባል ፡ በጎቹን ፡ ይሸልታል ፡ የሚል ፡ ወሬ ፡
፭ ሰማ ። ዳዊትም ፡ አሥር ፡ ጕልማሶች ፡ ላከ ፡ ለጕ
ልማሶችም ፡ አለ ፡— ወደ ፡ ቀርሜሎስ ፡ ወጥታ

ችሁ ፡ ወደ ፡ ናባል ፡ ሂዱ ፥ በስሜም ፡ ስለ ፡
፮ ሰላም ፡ ጠይቁት ፤ እንዲህም ፡ በሉት ፡— በደ
ኅንነት ፡ ኑር ፥ ለአንተና ፡ ለቤትህም ፡ ለአንተም ፡
፯ ላሉት ፡ ሁሉ ፡ ሰላም ፡ ይሁን ። አሁንም ፡ በጎ
ችህን ፡ እንድትሸልት ፡ ሰምቻለሁ ፤ እረኞች
ህም ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ነበሩ ፥ ከቶ ፡ አልበደል
ናቸውም ፤ በቀርሜሎስም ፡ በተቀመጡበት ፡
ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ከመንጋው ፡ አንዳች ፡ አልጐደ
፰ ለባቸውም ። ጕልማሶችህን ፡ ጠይቃቸው ፥
እነርሱም ፡ ይነግሩሃል ፤ አሁንም ፡ እንግዲህ ፡
በመልካም ፡ ቀን ፡ መጥተንብሃልና ፡ ጕልማሶች ፡
በፊትህ ፡ ሞገስ ፡ ያግኙ ፤ በእጅህም ፡ ከተገ
ኘው ፡ ለባሪያዎችህና ፡ ለልጅህ ፡ ለዳዊት ፥ እባ
ክህ ፥ ስጥ ።

፱ የዳዊትም ፡ ጕልማሶች ፡ መጡ ፥ ይህንም ፡
ቃል ፡ ሁሉ ፡ በዳዊት ፡ ስም ፡ ለናባል ፡ ነገረው ፡
፲ ዝም ፡ አሉ ። ናባልም ፡ ለዳዊት ፡ ባሪያዎች ፡—
ዳዊት ፡ ማን ፡ ነው ? የእሴይስ ፡ ልጅ ፡ ማን ፡ ነው ?
እያንዳንዳቸው ፡ ከጌቶቻቸው ፡ የኰበለሉ ፡ ባሪያ
፲፩ ዎች ፡ ዛሬ ፡ ብዙዎች ፡ ናቸው ። እንጀራዬንና ፡
የወይን ፡ ጠጄን ፡ ለሸላቾቼም ፡ ያረድሁትን ፡
ሥጋ ፡ ወስጄ ፡ ከወዴት ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ለማላ
ውቃቸው ፡ ሰዎች ፡ እሰጣለሁን ? ብሎ ፡ መለሰ
፲፪ ላቸው ። የዳዊትም ፡ ጕልማሶች ፡ ዞረው ፡ በመ
ጡበት ፡ መንገድ ፡ ተመለሱ ፥ መጥተውም ፡
፲፫ ይህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ለዳዊት ፡ ነገሩት ። ዳዊትም ፡
ሰዎቹን ፡— ሁላችሁ ፡ ሰይፋችሁን ፡ ታጠቁ ፡
አላቸው ። ሁሉም ፡ ሰይፋቸውን ፡ ታጠቁ ፥
ዳዊትም ፡ ሰይፉን ፡ ታጠቀ ፤ አራት ፡ መቶ ፡
ሰዎችም ፡ ዳዊትን ፡ ተከትለው ፡ ወጡ ፥ ሁለት ፡
መቶውም ፡ በዕቃው ፡ ዘንድ ፡ ተቀመጡ ።

፲፬ ከብላቴኖቹ ፡ አንዱ ፡ ለናባል ፡ ሚስት ፡ ለአ
ቢግያ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ነገራት ፡— እነሆ ፥
ዳዊት ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ሳለ ፡ ጌታችንን ፡ ሊባ
ርኩ ፡ መልእክተኞች ፡ ላከ ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ ሰደባ
፲፭ ቸው ። እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡
እጅግ ፡ መልካም ፡ ነበሩ ፤ አልበደሉንምም ፥
ከእነርሱም ፡ በሄድንበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ በም
ድረ ፡ በዳ ፡ ሳለን ፡ አንዳች ፡ አልጠፋብንም ፤
፲፮ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ሆነን ፡ መንጋውን ፡ በጠበቅን
በት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ሌሊትና ፡ ቀን ፡ አጥር ፡
፲፯ ሆነውን ፡ ነበር ። ስለዚህም ፡ በጌታችንና ፡ በቤቱ ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እንዲመጣ ፡ ተቈርጦ
አልና ፥ እርሱ ፡ ምናምንቴ ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡
ማንም ፡ ሊናገረው ፡ አይችልምና ፡ የምታደር
ጊውን ፡ ተመልከቺና ፡ እወቂ ።

፲፰ አቢግያም ፡ ፈጥና ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ እንጀራ ፥
ሁለት ፡ አቁማዳ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፥ አምስትም ፡
የተዘጋጁ ፡ በጎች ፥ አምስትም ፡ መስፈሪያ ፡
ጥብስ ፡ እሸት ፥ አንድ ፡ መቶ ፡ ዘለላ ፡ ዘቢብ ፥
ሁለት ፡ መቶም ፡ የበለስ ፡ ጥፍጥፍ ፡ ወሰደች ፥ በአ
፲፱ ህዮችም ፡ ላይ ፡ አስጫነች ። ለብላቴኖችዋም ፡—
አስቀድማችሁ ፡ በፊቴ ፡ ሂዱ ፥ እነሆም ፥ እከተ
ላችኋለሁ ፡ አለች ። ይህንም ፡ ለባልዋ ፡ ለናባል ፡
አልነገረችውም ። ፳ እርስዋም ፡ በአህያዋ ፡ ላይ ፡
ተቀምጣ ፡ በተራራው ፡ ላይ ፡ በተሰወረ ፡ ስፍራ ፡
በወረደች ፡ ጊዜ ፥ እነሆ ፥ ዳዊትና ፡ ሰዎቹ ፡ ወደ ፡
እርስዋ ፡ ወረዱ ፤ እርስዋም ፡ ተገናኘቻቸው ።
፳፩ ዳዊትም ፡— ለዚህ ፡ ሰው ፡ ከሆነው ፡ ሁሉ ፡
አንድ ፡ ነገር ፡ እንዳይጠፋበት ፡ በእውነት ፡ ከብ
ቱን ፡ ሁሉ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ በከንቱ ፡ ጠበቅሁ ፥
እርሱም ፡ ስለ ፡ በጎነቴ ፡ ክፋት ፡ መለሰልኝ ።
፳፪ ለእርሱም ፡ ከሆነው ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ነገ ፡ ጥዋት ፡
ድረስ ፡ አንድ ፡ ወንድ ፡ ስንኳ ፡ ብተው ፥ እግዚ
አብሔር ፡ በዳዊት ፡ ላይ ፡ እንዲህ ፡ ያድርግ ፡
እንዲህም ፡ ይጨምር ፡ ብሎ ፡ ነበር ።

፳፫ አቢግያም ፡ ዳዊትን ፡ ባየች ፡ ጊዜ ፡ ከአህያዋ ፡
ላይ ፡ ፈጥና ፡ ወረደች ፥ በዳዊትም ፡ ፊት ፡ በግ
ምባርዋ ፡ ወደቀች ፥ በምድርም ፡ ላይ ፡ እጅ ፡
፳፬ ነሣች ። በእግሩም ፡ ላይ ፡ ወደቀች ፥ እንዲህም ፡
አለች ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡ ኃጢአት ፡ በእኔ ፡
ላይ ፡ ይሁን ፤ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ በጆሮህ ፡ ልናገር ፥
፳፭ የባሪያህንም ፡ ቃል ፡ አድምጥ ። በዚህ ፡ ምና
ምንቴ ፡ ሰው ፡ በናባል ፡ ላይ ፡ ጌታዬ ፡ ልቡን ፡
እንዳይጥል ፡ እለምንሃለሁ ፤ እንደ ፡ ስሙ ፡ እን
ዲሁ ፡ እርሱ ፡ ነው ፤ ስሙ ፡ ናባል ፡ ነው ፥ ስን
ፍናም ፡ አድሮበታል ፤ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ግን ፡ ከአ
ንተ ፡ የተላኩትን ፡ የጌታዬን ፡ ጕልማሶች ፡
፳፮ አላየሁም ። አሁንም ፥ ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ ሕያው ፡
እግዚአብሔርን ! በሕያው ፡ ነፍስህም ፡ እምላ
ለሁ ! ወደ ፡ ደም ፡ እንዳትገባ ፥ እጅህም ፡ ራስህን ፡
እንዳታድን ፡ የከለከለህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ፤
አሁንም ፡ ጠላቶችህና ፡ በጌታዬ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡
፳፯ የሚሹ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ናባል ፡ ይሁኑ ። አሁንም ፡
ባሪያህ ፡ ወደ ፡ ጌታዬ ፡ ያመጣችው ፡ ይህ ፡ መተ
ያያ ፡ ጌታዬን ፡ ለሚከተሉ ፡ ጕልማሶች ፡ ይሰጥ ።
፳፰ የእግዚአብሔርን ፡ ጦርነት ፡ ስለምትዋጋ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ በእውነት ፡ ለጌታዬ ፡ የታመነ ፡
ቤት ፡ ይሠራልና ፡ የእኔን ፡ የባሪያህን ፡ ኃጢአት ፥
እባክህ ፥ ይቅር ፡ በል ፤ በዘመንህም ፡ ሁሉ ፡
፳፱ ክፋት ፡ አይገኝብህም ። ያሳድድህ ፡ ዘንድ ፡
ነፍስህንም ፡ ይሻ ፡ ዘንድ ፡ ሰው ፡ ቢነሣ ፥ የጌታዬ ፡
ነፍስ ፡ በሕያዋን ፡ ወገን ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ ዘንድ ፡ የታሰረች ፡ ትሆናለች ፤ የጠ
ላቶችህንም ፡ ነፍስ ፡ ከወንጭፍ ፡ እንደሚጣል ፡
፴ እንዲሁ ፡ ይጥላታል ። እግዚአብሔርም ፡ ለጌ
ታዬ ፡ የተናገረውን ፡ ቸርነት ፡ ሁሉ ፡ በደረገልህ ፡
ጊዜ ፥ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ አድርጎ ፡
፴፩ በሰነሣህ ፡ ጊዜ ፥ አንተ ፡ በከንቱ ፡ ደም ፡ እንዳ
ላፈሰስህ ፥ በገዛ ፡ እጅህም ፡ እንዳልተከስህ ፡
ይህ ፡ ዕንቅፋትና ፡ የሕሊና ፡ ጸጸት ፡ በጌታዬ ፡
አይሆንብህም ፤ እግዚአብሔርም ፡ ለጌታዬ ፡
በጎ ፡ በደረገልህ ፡ ጊዜ ፥ ባሪያህን ፡ አስብ ።

፴፪ ዳዊትም ፡ አቢግያን ፡ አላት ፡— ዛሬ ፡ እኔን ፡
ለመገናኘት ፡ አንቺን ፡ የሰደደ ፡ የእስራኤል ፡
፴፫ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ። ወደ ፡
ደም ፡ እንዳልሄድ ፥ በእጄም ፡ በቀል ፡ እንዳላ
ደርግ ፡ ዛሬ ፡ የከለከለኝ ፡ አእምሮሽ ፡ የተመሰ

ገነ ፡ ይሁን ÷ አንቺም ፡ የተመሰገንሽ ፡ ሁኚ ። ፴፬ ነገር ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ እንዳላደርግብሽ ፡ የከለከለኝ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! እኔን ፡ ለመገናኘት ፡ ፈጥነሽ ፡ ባልመጣሽ ፡ ኖሮ ÷ እስኪነጋ ፡ ድረስ ፡ ለናባል ፡ አንድ ፡ ወንድ ፡ ስንኳ ፡ ባልቀረውም ፡ ነበር ። ፴፭ ዳዊትም ፡ ያመጣችውን ፡ ከእጅዋ ፡ ተቀብሎ ፡— በደኅና ፡ ወደ ፡ ቤትሽ ፡ ሂጂ ፤ እነሆ ÷ ቃልሽን ፡ ሰማሁ ÷ ፊትሽንም ፡ አከበርሁ ፡ አላት ።

፴፮ አቢግያም ፡ ወደ ፡ ናባል ፡ መጣች ፤ እነሆም ÷ በቤቱ ፡ እንደ ፡ ንጉሥ ፡ ግብዣ ፡ ያለ ፡ ግብዣ ፡ ያደርግ ፡ ነበር ፤ ናባልም ፡ እጅግ ፡ ሰክሮ ፡ ነበርና ፡ ልቡ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ነበር ፤ ስለዚህም ፡ እስኪነጋ ፡ ድረስ ፡ ታናሽ ፡ ነገር ፡ ወይም ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡ አልነገረችውም ፡ ነበር ። ፴፯ በነጋውም ፡ የጠጁ ፡ ስካር ፡ ከናባል ፡ ባለፈ ፡ ጊዜ ፡ ሚስቱ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ነገረችው ፤ ልቡም ፡ በውስጡ ፡ ሞተ ÷ እንደ ፡ ድንጋይም ፡ ሆነ ፤ ፴፰ ከአሥር ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ ናባልን ፡ ቀሠፈው ÷ እርሱም ፡ ሞተ ።

፴፱ ዳዊትም ፡ ናባል ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡— ከናባል ፡ እጅ ፡ የስድቤን ፡ ፍርድ ፡ የፈረደልኝ ÷ ባሪያውንም ፡ ከክፋት ፡ የጠበቀ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ፤ እግዚአብሔርም ፡ የናባልን ፡ ክፋት ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ መለሰ ፡ አለ ። ዳዊትም ፡ ልኮ ፡ ያገባት ፡ ዘንድ ፡ አቢግያን ፡ ተነጋገራት ። ፵ የዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡ ወደ ፡ ቀርሜሎስ ፡ ወደ ፡ አቢግያ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡— ዳዊት ፡ ያገባሽ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡ ልኮናል ፡ ብለው ፡ ነገሩአት ። ፵፩ ተነሥታም ፡ በግምባርዋ ፡ ወድቃ ፡ እጅ ፡ ነሣችና ፡— እነሆ ÷ እኔ ፡ ገረድህ ፡ የጌታዬን ፡ ሎሌዎች ፡ እግር ፡ አጥብ ፡ ዘንድ ፡ አገልጋይ ፡ ነኝ ፡ አለች ። ፵፪ አቢግያም ፡ ፈጥና ፡ ተነሣች ፤ በአህያም ፡ ላይ ፡ ተቀመጠች ÷ አምስቱም ፡ ገረዶችዋ ፡ ተከተሉአት ፤ የዳዊትንም ፡ መልእክተኞች ፡ ተከትላ ፡ ሄደች ÷ ሚስትም ፡ ሆነችው ።

፵፫ ዳዊትም ፡ ደግሞ ፡ ኢይዝራኤላዊቱን ፡ አኪናሆምን ፡ ወሰደ ፤ ሁለቱም ፡ ሚስቶች ፡ ሆኑለት ። ፵፬ ሳኦል ፡ ግን ፡ የዳዊትን ፡ ሚስት ፡ ልጁን ፡ ሜልኮልን ፡ አገሩ ፡ ጋሊም ፡ ለነበረው ፡ ለሌሳ ፡ ልጅ ፡ ለፈልጢ ፡ ሰጥቶ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩ የዚፍ ፡ ሰዎችም ፡ ወደ ፡ ጊብዓ ፡ ወደ ፡ ሳኦል ፡ መጥተው ፡— እነሆ ÷ ዳዊት ፡ በየሴሞን ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ባለው ፡ በኤኬላ ፡ ኮረብታ ፡ ላይ ፡ ተሸሽጎአል ፡ አሉት ። ፪ ሳኦልም ፡ ተነሥቶ ፡ ዳዊትን ፡ በዚፍ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ይሻ ፡ ዘንድ ፡ ከእስራኤል ፡ የተመረጡ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ዚፍ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወረደ ። ፫ ሳኦልም ፡ በየሴሞን ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ባለው ፡ በኤኬላ ፡ ኮረብታ ፡ ላይ ፡ በመንገዱ ፡ አጠገብ ፡ ሰፈረ ። ዳዊትም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ውስጥ ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ÷ ሳኦልም ፡ በስተ ፡ ኋላው ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ አየ ። ፬ ዳዊትም ፡ ሰላዮች ፡ ሰደደ ÷ ሳኦልም ፡ ወደዚህ ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ በእርግጥ ፡ አወቀ ። ፭ ዳዊትም ፡ ተነሥቶ ፡ ሳኦል ፡ ወደ ፡ ሰፈረበት ፡ ቦታ ፡ መጣ ፤ ሳኦልና ፡ የሠራዊቱ ፡ አለቃ ፡ የኔር ፡ ልጅ ፡ አበኔርም ፡ የተኙበትን ፡ ስፍራ ፡ አየ ፤ ሳኦልም ፡ በሰፈሩ ፡ ውስጥ ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ፤ ሕዝቡም ፡ በዙሪያው ፡ ሰፍሮ ፡ ነበር ።

፮ ዳዊትም ፡ ኬጢያዊውን ፡ አቢሜሌክንና ፡ የጽሩያን ፡ ልጅ ፡ የኢዮአብን ፡ ወንድም ፡ አቢሳን ፡— ወደ ፡ ሳኦል ፡ ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ የሚወርድ ፡ ማን ፡ ነው ? ብሎ ፡ ጠየቃቸው ፤ አቢሳም ፡— እኔ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ እወርዳለሁ ፡ አለ ። ፯ ዳዊትና ፡ አቢሳም ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ በሌሊት ፡ መጡ ፤ እነሆም ÷ ሳኦል ፡ ጦሩ ፡ በራሱ ፡ አጠገብ ፡ በምድር ፡ ተተክሎ ፡ በሰፈሩ ፡ ውስጥ ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ፤ አበኔርና ፡ ሕዝቡም ፡ በዙሪያው ፡ ተኝተው ፡ ነበር ። ፰ አቢሳም ፡ ዳዊትን ፡— ዛሬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጠላትህን ፡ በእጅህ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶታል ፤ አሁንም ፡ እኔ ፡ በጦር ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ከምድር ፡ ጋር ፡ ላጣብቀው ÷ ሁለተኛም ፡ አያዳግመኝም ፡ አለው ። ፱ ዳዊትም ፡ አቢሳን ፡— እግዚአብሔር ፡ በቀባው ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ የሚዘረጋ ፡ ንጹሕ ፡ አይሆንምና ፡ አትግደለው ፡ አለው ። ፲ ደግሞም ፡ ዳዊት ፡— ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! እግዚአብሔር ፡ ይመታዋል ÷ ወይም ፡ ቀኑ ፡ ደርሶ ፡ ይሞታል ÷ ወይም ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ ወርዶ ፡ ይገደላል ፤ ፲፩ እኔ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ በቀባው ፡ ላይ ፡ እጄን ፡ እዘረጋ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእኔ ፡ ያርቀው ፤ አሁንም ፡ በራሱ ፡ አጠገብ ፡ ያለውን ፡ ጦርና ፡ የውኃውን ፡ መንቀል ፡ ይዘህ ፡ እንሂድ ፡ አለ ። ፲፪ ዳዊትም ፡ በሳኦል ፡ ራስ ፡ አጠገብ ፡ የነበረውን ፡ ጦርና ፡ የውኃውን ፡ መንቀል ፡ ወሰደ ፤ ማንም ፡ ሳያይ ፡ ሳያውቅም ፡ ሄዱ ፤ ከእግዚአብሔርም ፡ ዘንድ ፡ ከባድ ፡ እንቅልፍ ፡ ወድቆባቸው ፡ ነበርና ፡ ሁሉ ፡ ተኝተው ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ የነቃ ፡ አልነበረም ።

፲፫ ዳዊትም ፡ ወደዚያ ፡ ተሻገረ ፤ በተራራውም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ርቆ ፡ ቆመ ፤ በመካከላቸውም ፡ ሰፊ ፡ ስፍራ ፡ ነበረ ። ፲፬ ዳዊትም ፡ ለሕዝቡና ፡ ለኔር ፡ ልጅ ፡ ለአበኔር ፡— አበኔር ፡ ሆይ ÷ አትመልስምን ? ብሎ ፡ ጮኸ ። አበኔርም ፡ መልሶ ፡— ለንጉሡ ፡ የምትጮኸው ፡ አንተ ፡ ማን ፡ ነህ ? አለ ። ፲፭ ዳዊትም ፡ አበኔርን ፡— አንተ ፡ ጕልማሳ ፡ አይደለህምን ? በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ አንተን ፡ የሚመስል ፡ ማን ፡ ነው ? ጌታህን ፡ ንጉሡን ፡ ለመግደል ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ገብቶ ፡ ነበርና ፡ ጌታህን ፡ ንጉሡን ፡ የማትጠብቅ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ነው ? ፲፮ ይህ ፡ ያደረግኸው ፡ ነገር ፡ መልካም ፡ አይደለም ፤ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! እናንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ የቀባውን ፡ ጌታችሁን ፡ አልጠበቃችሁምና ፡ ሞት ፡ ይገባችኋል ፤ አሁንም ፡ የንጉሡ ፡ ጦርና ፡ በራሱ ፡ አጠገብ ፡ የነበረው ፡ የውኃው ፡

መንቀል ፡ የት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ተመልከት ፡
አለው ።
፲፯ ሳኦልም ፡ የዳዊት ፡ ድምፅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
አውቆ ፦ ልጄ ፡ ዳዊት ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡ ድምፅህ ፡
ነውን ? አለው ። ዳዊትም ፦ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡
፲፰ ሆይ ፥ ድምፄ ፡ ነው ፡ አለው ። ደግሞ ፡ አለ ፦
ጌታዬ ፡ በሪያውን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ያሳድዳል ?
ምን ፡ አደረግሁ ? ምንስ ፡ ክፋት ፡ በእጄ ፡ ላይ ፡
፲፱ ተገኘብኝ ? አሁንም ፡ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥
የእኔን ፡ የባሪያህን ፡ ቃል ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡ እለ
ምንሃለሁ ፤ እግዚአብሔር ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ አስነሥ
ቶህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ቁርባንን ፡ ይቀበል ፤ የሰው ፡
ልጆች ፡ ግን ፡ ቢሆኑ ፦ ሂድ ፡ ሌሎችን ፡ አማ
ልክት ፡ አምልክ ፡ ብለው ፡ በእግዚአብሔር ፡
ርስት ፡ ላይ ፡ እንዳልቀመጥ ፡ ዛሬ ፡ ጥለውኛልና ፡
፳ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ርጉማን ፡ ይሁኑ ። አሁ
ንም ፡ በተራራው ፡ ላይ ፡ ሰው ፡ ቆቅን ፡ እንደ
ሚሻ ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ነፍሴን ፡ ለመሻት ፡
ወጥቶአልና ፡ ደሜ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ርቆ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አይፍሰስ ።
፳፩ ሳኦልም ፦ በድያለሁ ፤ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ዳዊት ፥
ተመለስ ፤ ዛሬ ፡ ነፍሴ ፡ በዓይንህ ፡ ፊት ፡ ከብራ
ለችና ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ክፉ ፡ አላደርግብህም ፤
እነሆ ፥ ስንፍና ፡ አድርጌአለሁ ፥ እጅግ ፡ ብዙም ፡
፳፪ ስቻለሁ ፡ አለ ። ዳዊትም ፡ መልሶ ፡ አለ ፦ የን
ጉሥ ፡ ጦር ፡ እነሆ ፥ ከብላቴኖችም ፡ አንድ ፡
፳፫ ይምጣና ፡ ይውሰዳት ። ዛሬም ፡ እግዚአብሔር ፡
በእጄ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶህ ፡ ሳለ ፡ እግዚአብሔር ፡
በቀባው ፡ ላይ ፡ እጄን ፡ እዘረጋ ፡ ዘንድ ፡ አል
ወደድሁምና ፡ ለሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንደ ፡ ጽድቁና ፡ እንደ ፡ እምነቱ ፡ ፍዳ
፳፬ ውን ፡ ይከፍለው ። ነፍስህም ፡ ዛሬ ፡ በዓይኔ ፡
ፊት ፡ እንደ ፡ ከበረች ፡ እንዲሁ ፡ ነፍሴ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ዓይን ፡ ፊት ፡ ትክበር ፥ ከመከ
፳፭ ራም ፡ ሁሉ ፡ ያድነኝ ። ሳኦል ፡ ዳዊትን ፦ ልጄ ፡
ዳዊት ፡ ሆይ ፥ ቡሩክ ፡ ሁን ፤ ማድረግን ፡ ታደር
ጋለህ ፥ መቻልንም ፡ ትችላለህ ፡ አለው ። ዳዊ
ትም ፡ መንገዱን ፡ ሄደ ፥ ሳኦልም ፡ ወደ ፡ ስፍ
ራው ፡ ተመለሰ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

፩ ዳዊትም ፡ በልቡ ፦ አንድ ፡ ቀን ፡ በሳኦል ፡ እጅ ፡
እጠፋለሁ ፡ ወደ ፡ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ምድር ፡
ከመሸሽ ፡ በቀር ፡ የሚሻለኝ ፡ የለም ፤ ሳኦልም ፡
በእስራኤል ፡ አውራጃ ፡ ሁሉ ፡ እኔን ፡ መሻት ፡
ይተዋል ፥ እንዲሁም ፡ ከእጁ ፡ እድናለሁ ፡ አለ ።
፪ ዳዊትም ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ ስድስቱ ፡
መቶ ፡ ሰዎች ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ ጌት ፡ ንጉሥ ፡
፫ ወደ ፡ አሜህ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ አንኩስ ፡ አለፉ ። ዳዊ
ትና ፡ ሰዎቹም ፡ እያንዳንዳቸው ፡ ከነ ፡ ቤተ ፡ ሰቡ ፡
ከአንኩስ ፡ ጋር ፡ በጌት ፡ ውስጥ ፡ ተቀመጡ ፤ ከዳ
ዊትም ፡ ጋር ፡ ኢይዝራኤላዊቱ ፡ አኪናሆምና ፡
የቀርሜሎሳዊው ፡ የናባል ፡ ሚስት ፡ አቢግያ ፡
፬ ሁለቱ ፡ ሚስቶቹ ፡ ነበሩ ። ሳኦልም ፡ ዳዊት ፡
ወደ ፡ ጌት ፡ እንደ ፡ ኰበለለ ፡ ሰማ ፤ ከዚያም ፡
በኋላ ፡ ደግሞ ፡ አልፈለገውም ።
፭ ዳዊትም ፡ አንኩስን ፦ በዓይንህ ፡ ፊት ፡
ሞገስ ፡ አግኝቼ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በዚህ ፡ አገር ፡
በአንዲቱ ፡ ከተማ ፡ የምቀመጥበት ፡ ስፍራ ፡
ስጠኝ ፤ ስለ ፡ ምን ፡ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ከአንተ ፡
ጋር ፡ በንጉሥ ፡ ከተማ ፡ እቀመጣለሁ ? አለው ።
፮ በዚያም ፡ ቀን ፡ አንኩስ ፡ ጺቅላግን ፡ ሰጠው ፤ ስለ
ዚህም ፡ ጺቅላግ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ለይሁዳ ፡
፯ ነገሥታት ፡ ሆነች ። ዳዊትም ፡ በፍልስጥኤማው
ያን ፡ አገር ፡ የተቀመጠበት ፡ የዘመን ፡ ቍጥር ፡
አንድ ፡ ዓመት ፡ ከአራት ፡ ወር ፡ ነበረ ።
፰ ዳዊትና ፡ ሰዎቹም ፡ ወጥተው ፡ በጌሹራውያ
ንና ፡ በጌርዛውያን ፡ በአማሌቃውያንም ፡ ላይ ፡
ዘመቱ ፤ እነዚህም ፡ እስከ ፡ ሱር ፡ እስከ ፡ ግብጽ ፡
ምድር ፡ ድረስ ፡ ባለው ፡ አገር ፡ ድሮውኑ ፡
፱ ተቀምጠው ፡ ነበር ። ዳዊትም ፡ ምድሪቱን ፡
መታ ፤ ወንድ ፡ ሆነ ፡ ሴትም ፡ ሆነ ፡ ማንንም ፡
በሕይወት ፡ አልተወም ፤ በጎችንና ፡ ላሞችን ፡
አህያዎችንና ፡ ግመሎችን ፡ ልብስንም ፡ ማረከ ፥
፲ ተመልሶም ፡ ወደ ፡ አንኩስ ፡ መጣ ። አንኩ
ስም ፦ ዛሬ ፡ በማን ፡ ላይ ፡ ዘመታችሁ ? አለ ፤
ዳዊትም ፦ በይሁዳ ፡ ደቡብ ፥ በይረሕምኤ
ላውያንም ፡ ደቡብ ፥ በቄናውያንም ፡ ደቡብ ፡
፲፩ ላይ ፡ ዘመትን ፡ አለ ። ዳዊት ፡ እንዲህ ፡ አደ
ረገ ፡ በፍልስጥኤማውያንም ፡ አገር ፡ በሚቀ
መጥበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ልማዱ ፡ ይህ ፡ ነበረ ፡
ብለው ፡ እንዳይናገሩብን ፡ ብሎ ፡ ዳዊት ፡ ወደ ፡
ጌት ፡ ያመጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ወንድም ፡ ሆነ ፡
ሴትም ፡ ሆነ ፡ ማንንም ፡ በሕይወት ፡ አልተወም ።
፲፪ አንኩስም ፦ በሕዝቡ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡
እጅግ ፡ የተጠላ ፡ ሆኖአል ፤ ስለዚህም ፡ ለዘላ
ለም ፡ ባሪያ ፡ ይሆነኛል ፡ ብሎ ፡ ዳዊትን ፡ አመ
ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በዚያ ፡ ወራት ፡ ከእስራ
ኤል ፡ ጋር ፡ ይዋጉ ፡ ዘንድ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡
ጭፍሮቻቸውን ፡ ለሰልፍ ፡ ሰበሰቡ ፤ አንኩ
ስም ፡ ዳዊትን ፦ አንተና ፡ ሰዎችህ ፡ ከእኔ ፡
ጋር ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ እንድትወጡ ፡ በእርግጥ ፡
፪ እወቅ ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ አንኩስን ፦ አሁን ፡
ባሪያህ ፡ የሚያደርገውን ፡ ታያለህ ፡ አለው ።
አንኩስም ፡ ዳዊትን ፦ እንግዲህ ፡ በዘመኑ ፡
ሁሉ ፡ ራሴን ፡ ጠባቂ ፡ አደርግሃለሁ ፡ አለው ።
፫ ሳሙኤል ፡ ግን ፡ ሞቶ ፡ ነበር ፥ እስራኤልም ፡
ሁሉ ፡ አልቅሰውለት ፡ ነበር ፥ በከተማውም ፡
በአርማቴም ፡ ቀብረውት ፡ ነበር ። ሳኦልም ፡
መናፍስት ፡ ጠሪዎችንና ፡ ጠንቋዮችን ፡ ከም
፬ ድር ፡ አጥፍቶ ፡ ነበር ። ፍልስጥኤማውያንም ፡
ተሰብስበው ፡ መጡ ፡ በሱነምም ፡ ሰፈሩ ፤ ሳኦ
ልም ፡ እስራኤልን ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰበ ፥ በጌልቦ
፭ ዓም ፡ ሰፈሩ ። ሳኦልም ፡ የፍልስጥኤማውያንን ፡
ጭፍራ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ፈራ ፥ ልቡም ፡ እጅግ ፡

፮ ተንቀጠቀጠ ። ሳኦልም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠየቀ ፤ እግዚአብሔርም ፡ በሕልም ፡ ወይም ፡ በኡሪም ፡ ወይም ፡ በነቢያት ፡ አልመለሰለትም ።

፯ ሳኦልም ፡ ባሪያዎቹን ፦ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ሄጄ ፡ እጠይቅ ፡ ዘንድ ፡ መናፍስትን ፡ የምትጠራ ፡ ሴት ፡ ፈልጉልኝ ፡ አላቸው ፤ ባሪያዎቹም ፦ እነሆ ፥ መናፍስትን ፡ የምትጠራ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ በዓይንዶር ፡ አለች ፡ አሉት ።

፰ ሳኦልም ፡ መልኩን ፡ ለውጦ ፡ ሌላ ፡ ልብስም ፡ ለብሶ ፡ ሄደ ፥ ሁለትም ፡ ሰዎች ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበሩ ፥ በሌሊትም ፡ ወደ ፡ ሴቲቱ ፡ መጡ ። እርሱም ፦ እባክሽ ፥ በመናፍስት ፡ አምዋርቺ ፱ ልኝ ፥ የምልሽንም ፡ አስነሽልኝ ፡ አላት ። ሴቲቱም ፦ እነሆ ፥ መናፍስት ፡ ጠሪዎችንና ፡ ጠንቋዮችን ፡ ከምድር ፡ እንዳጠፋ ፡ ሳኦል ፡ ያደረገውን ፡ ታውቃለህ ፤ ስለ ፡ ምን ፡ እኔን ፡ ለማስገደል ፡ ወጥመድ ፡ ለነፍሴ ፡ ታደርጋለህ? አለችው ።

፲ ሳኦልም ፦ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! በዚህ ፡ ነገር ፡ ቅጣት ፡ አያገኝሽም ፡ ብሎ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ማለላት ።

፲፩ ሴቲቱም ፦ ማንን ፡ ላስነሣልህ? አለች ፤ እርሱም ፦ ሳሙኤልን ፡ አስነሽልኝ ፡ አለ ።

፲፪ ሴቲቱም ፡ ሳሙኤልን ፡ ባየች ፡ ጊዜ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ጮኸች ፤ ሴቲቱም ፡ ሳኦልን ፦ አንተ ፡ ሳኦል ፡ ስትሆን ፡ ስምን ፡ አታለልኸኝ ? ብላ ፡ ተናገረችው ።

፲፫ ንጉሡም ፦ አትፍሪ ፤ ያየሽው ፡ ምንድር ፡ ነው ? አላት ። ሴቲቱም ፡ ሳኦልን ፦ አማልክት ፡ ከምድር ፡ ሲወጡ ፡ አየሁ ፡ አለችው ።

፲፬ እርሱም ፦ መልኩ ፡ ምን ፡ ዓይነት ፡ ነው ? አላት ። እርስዋም ፦ ሽማግሌ ፡ ሰው ፡ ወጣ ፤ መጐናጸፊያም ፡ ተጐናጽፎአል ፡ አለች ። ሳኦልም ፡ ሳሙኤል ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አወቀ ፥ በፊቱም ፡ ተጐንበሰ ፥ በምድርም ፡ ላይ ፡ እጅ ፡ ነሣ ።

፲፭ ሳሙኤልም ፡ ሳኦልን ፦ ለምን ፡ አወክኸኝ ? ለምንስ ፡ አስነሣኸኝ ? አለው ። ሳኦልም ፡ መልሶ ፦ ፍልስጥኤማውያን ፡ ይወጉኛልና ፡ እጅግ ፡ ተጨንቄአለሁ ፥ እግዚአብሔርም ፡ ከእኔ ፡ ርቆአል ፤ በነቢያት ፡ ወይም ፡ በሕልም ፡ አልመለሰልኝም ፤ ስለዚህም ፡ የማደርገውን ፡ ታስታውቀኝ ፡ ዘንድ ፡ ጠራሁህ ፡ አለው ።

፲፮ ሳሙኤልም ፡ አለ ፦ እግዚአብሔር ፡ ከራቀህ ፡ ጠላትም ፡ ከሆነህ ፡ ለምን ፡ ትጠይቀኛለህ ?

፲፯ እግዚአብሔርም ፡ በቃሌ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ አድርጎአል ፤ እግዚአብሔርም ፡ መንግሥትህን ፡ ከእጅህ ፡ ነጥቆ ፡ ለጎረቤትህ ፡ ለዳዊት ፡ ሰጥቶታል ።

፲፰ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አልሰማህምና ፥ በአማሌቅም ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ የሆነ ፡ ቍጣውን ፡ አላደረግህምና ፡ ስለዚህ ፡ ዛሬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ አድርጎብሃል ።

፲፱ እግዚአብሔርም ፡ እስራኤልን ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ በፍልስጥኤማውያን ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣል ፤ ነገም ፡ አንተና ፡ ልጆችህ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ትሆናላችሁ ፤ እግዚአብሔርም ፡ የእስራኤልን ፡ ጭፍራ ፡ ደግሞ ፡ በፍልስጥኤማውያን ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣል ።

፳ ሳኦልም ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በቁመቱ ፡ ሙሉ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፥ ከሳሙኤልም ፡ ቃል ፡ የተነሣ ፡ እጅግ ፡ ፈራ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ሁሉ ፡ በዚያም ፡ ሌሊት ፡ ሁሉ ፡ እንጀራ ፡ አልበላምና ፡ ኃይል ፡ አልቀረለትም ።

፳፩ ሴቲቱም ፡ ወደ ፡ ሳኦል ፡ መጣች ፥ እጅግም ፡ ደንግጦ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ አይታ ፦ እነሆ ፥ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ቃልህን ፡ ሰማሁ ፥ ነፍሴንም ፡ በእጄ ፡ ጣልሁ ፥ የነገርኸኝንም ፡ ቃል ፡ ሰማሁ ።

፳፪ አሁን ፡ እንግዲህ ፡ አንተ ፡ ደግሞ ፡ የባሪያህን ፡ ቃል ፡ እንድትሰማ ፡ እለምንሃለሁ ፥ በፊትህም ፡ ቍራሽ ፡ እንጀራ ፡ ላኑርልህ ፤ በመንገድም ፡ ስትሄድ ፡ ትበረታ ፡ ዘንድ ፡ ብላ ፡ አለችው ።

፳፫ እርሱ ፡ ግን ፦ አልበላም ፡ ብሎ ፡ እንቢ ፡ አለ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ባሪያዎቹና ፡ ሴቲቱ ፡ አስገደዱት ፥ ቃላቸውንም ፡ ሰማ ፤ ከምድርም ፡ ተነሥቶ ፡ በአልጋ ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ።

፳፬ ለሴቲቱም ፡ ማለፊያ ፡ እንቦሳ ፡ ነበራት ፤ ፈጥና ፡ አረደችው ፤ ዱቄቱንም ፡ ወስዳ ፡ ለወሰችው ፥ ቂጣም ፡ እንጀራ ፡ አድርጋ ፡ ጋገረችው ።

፳፭ በሳኦልና ፡ በባሪያዎቹም ፡ ፊት ፡ አቀረበችው ፤ በልተውም ፡ ተነሡ ፥ በዚያም ፡ ሌሊት ፡ ሄዱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

፩ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ጭፍሮቻቸውን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ አፌቅ ፡ ሰበሰቡ ፤ እስራኤላውያንም ፡ በኢይዝራኤል ፡ ባለው ፡ ውኃ ፡ ምንጭ ፡ አጠገብ ፡ ሰፈሩ ።

፪ የፍልስጥኤማውያንም ፡ አለቆች ፡ በመቶ ፡ በመቶ ፡ በሺህ ፡ በሺህ ፡ እየሆኑ ፡ ያልፉ ፡ ነበር ፤ ዳዊትና ፡ ሰዎቹም ፡ ከአንኩስ ፡ ጋር ፡ በኋለኛው ፡ ጭፍራ ፡ በኩል ፡ ያልፉ ፡ ነበር ።

፫ የፍልስጥኤማውያንም ፡ አለቆች ፦ እነዚህ ፡ ዕብራውያን ፡ በዚህ ፡ ምን ፡ ያደርጋሉ ? አሉ ፤ አንኩስም ፡ የፍልስጥኤማውያንን ፡ አለቆች ፦ ይህ ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ የሳኦል ፡ ባሪያ ፡ ዳዊት ፡ አይደለምን? እርሱም ፡ በእነዚህ ፡ ቀኖች ፡ በእነዚህ ፡ ዓመታት ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፥ ወደ ፡ እኔም ፡ ከተጠጋበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ምንም ፡ አላገኘሁበትም ፡ አላቸው ።

፬ የፍልስጥኤማውያን ፡ አለቆች ፡ ግን ፡ ተቆጥተው ፦ ይህ ፡ ሰው ፡ በስቀመጥኸው ፡ ስፍራ ፡ ይቀመጥ ፡ ዘንድ ፡ ይመለስ ፤ በሰልፉ ፡ ውስጥ ፡ ጠላት ፡ እንዳይሆነን ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ አይውረድ ፤ ከጌታው ፡ ጋር ፡ በምን ፡ ይታረቃል? የእነዚህን ፡ ሰዎች ፡ ራስ ፡ በመቍረጥ ፡ አይደለምን ?

፭ ወይስ ፡ ሴቶች ፦ ሳኦል ፡ ሺህ ፡ ገደለ ፥ ዳዊት ፡ እልፍ ፡ ገደለ ፡ ብለው ፡ በዘፈን ፡ የዘመሩለት ፡ ይህ ፡ ዳዊት ፡ አይደለምን ? አሉት ።

፮ አንኩስም ፡ ዳዊትን ፡ ጠርቶ ፦ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! አንተ ፡ ቀን ፡ ነህ ፥ ከእኔም ፡ ጋር ፡ በጭፍራው ፡ በኩል ፡ መውጣትህና ፡ መግባትህ ፡ በፊቴ ፡ መልካም ፡ ነው ፤ ወደ ፡ እኔም ፡ ከመጣህ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ አንዳች ፡ ክፋት ፡ አላገኘሁብህም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በአለቆች ፡ ዘንድ ፡ አልተወደድህም ።

፯ አሁንም ፡ ተመልሰህ ፡ በደኅና ፡ ሂድ ፥ በፍልስጥኤማውያንም ፡

አለቆች ፡ ዓይን ፡ ክፉት ፡ አታድርግ ፡ አለው ።

፰ ዳዊትም ፡ አንኩስን ፦ ምን ፡ አድርጌአለሁ ? ሄጄስ ፡ ከጌታዬ ፡ ከንጉሡ ፡ ጠላቶች ፡ ጋር ፡ እንዳልዋጋ ፥ በፊትህ ፡ ከተቀመጥሁ ፡ ጀምሬ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በእኔ ፡ በባሪያህ ፡ ምን ፡ አግ
፱ ኝተህብኛል ? አለው ። አንኩስም ፡ መልሶ ፡ ዳዊትን ፦ እንደ ፡ አምላክ ፡ መልእክተኛ ፡ በዓይኔ ፡ ፊት ፡ መልካም ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ አውቃለሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የፍልስጥኤማውያን ፡ አለቆች ፦ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ አይወጣም ፡
፲ አሉ ። አሁንም ፡ አንተ ፡ ከአንተም ፡ ጋር ፡ የመጡ ፡ የጌታህ ፡ ባሪያዎች ፡ ማልዳችሁ ፡ ተነሡ ፤ ሲነጋም ፡ ተነሥታችሁ ፡ ሂዱ ፡ አለው ።
፲፩ ዳዊትና ፡ ሰዎቹም ፡ ማልደው ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፥ ወደ ፡ ፍልስጥኤማውያንም ፡ አገር ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ ተነሡ ። ፍልስጥኤማውያንም ፡ ወደ ፡ ኢይዝራኤል ፡ ወጡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ዳዊትና ፡ ሰዎቹ ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ጺቅላግ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፥ አማሌቃውያን ፡ በደቡብ ፡ አገርና ፡ በጺቅላግ ፡ ላይ ፡ ዘምተው ፡ ነበር ፥ ጺቅላግንም ፡ መትተው ፡
፪ በእሳት ፡ አቃጥለዋት ፡ ነበር ፤ ሴቶቹንና ፡ በውስጥዋም ፡ የነበሩትን ፡ ሁሉ ፡ ከታናሽ ፡ እስከ ፡ ታላቅ ፡ ድረስ ፡ ማርከው ፡ ነበር ፤ ሁሉንም ፡ ወስደው ፡ መንገዳቸውን ፡ ሄዱ ፡ እንጂ ፡ አን
፫ ድስ ፡ እንኳ ፡ አልገደሉም ፡ ነበር ። ዳዊትና ፡ ሰዎቹም ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፥ እነሆ ፥ በእሳት ፡ ተቃጥላ ፥ ሚስቶቻቸውም ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውም ፡ ተማርከው ፡
፬ አገኙ ። ዳዊት ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩ ፡ ሕዝብ ፡ ድምፃቸውን ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡ ለማልቀስ ፡
፭ ኃይል ፡ እስኪያጡ ፡ ድረስ ፡ አለቀሱ ። የዳዊትም ፡ ሁለቱ ፡ ሚስቶቹ ፡ ኢይዝራኤላዊቱ ፡ አኪናሆምና ፡ የቀርሜሎሳዊው ፡ የናባል ፡ ሚስት ፡
፮ የነበረችው ፡ አቢግያ ፡ ተማርከው ፡ ነበር ። ስለ ፡ ወንዶችና ፡ ስለ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸው ፡ የሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ልብ ፡ ተቈጥቶ ፡ ነበርና ፡ ሕዝቡ ፡ ሊወግሩት ፡ ስለ ፡ ተናገሩ ፡ ዳዊት ፡ እጅግ ፡ ተጨነቀ ፤ ዳዊት ፡ ግን ፡ በአምላኩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ልቡን ፡ አበረታ ።

፯ ዳዊትም ፡ የአቢሜሌክን ፡ ልጅ ፡ ካህኑን ፡ አብያታርን ፦ ኤፉዱን ፡ አቅርብልኝ ፡ አለው ፤ አብ
፰ ያታርም ፡ ኤፉዱን ፡ ለዳዊት ፡ አቀረበለት ። ዳዊትም ፦ የእነዚህን ፡ ሠራዊት ፡ ፍለጋ ፡ ልከተልን ? አገኛቸዋለሁን ? ብሎ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠየቀ ፤ እርሱም ፦ ታገኛቸዋለህና ፥ ፈጽመህም ፡ ምርኮውን ፡ ትመልሳለህና ፡ ፍለጋቸውን ፡
፱ ተከተል ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ። ዳዊትም ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ሄዱ ፥ እስከ ፡ ባሦር ፡ ወንዝ ፡ ድረስም ፡ መጡ ፤
፲ ከእነርሱም ፡ የቀሩት ፡ በዚያ ፡ ተቀመጡ ። ዳዊትም ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ያሉት ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ አሳደዱ ፤ ሁለቱ ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ የባሦር ፡ ወንዝን ፡ መሻገር ፡ ደክመዋልና ፡ በኋላ ፡ ቀሩ ።

፲፩ በበረሀውም ፡ ውስጥ ፡ አንድ ፡ ግብጻዊ ፡ አገኙት ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ይዘውት ፡ መጡ ፤ እንጀራም ፡
፲፪ ሰጡትና ፡ በላ ፥ ውኃም ፡ አጠጡት ፤ ከበለሱም ፡ ጥፍጥፍ ፡ ቁራጭና ፡ ሁለት ፡ የወይን ፡ ዘለላ ፡ ሰጡት ፤ ሦስት ፡ ቀንና ፡ ሦስት ፡ ሌሊት ፡ እንጀራ ፡ አልበላም ፡ ውኃም ፡ አልጠጣም ፡ ነበርና ፡ በበላ ፡
፲፫ ጊዜ ፡ ነፍሱ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተመለሰች ። ዳዊትም ፦ አንተ ፡ የማን ፡ ነህ ? ከወዴት ፡ መጣህ ? አለው ። እርሱም ፦ እኔ ፡ የአማሌቃዊ ፡ ባሪያ ፡ ግብጻዊ ፡ ብላቴና ፡ ነኝ ፤ ከሦስት ፡ ቀንም ፡ በፊት ፡
፲፬ ታምሜ ፡ ነበርና ፡ ጌታዬ ፡ ጥሎኝ ፡ ሄደ ። እኛም ፡ በከሊታውያን ፡ ደቡብ ፥ በይሁዳም ፡ ምድር ፥ በካሌብም ፡ ደቡብ ፡ ላይ ፡ ዘመትን ፤ ጺቅላግ
፲፭ ንም ፡ በእሳት ፡ አቃጠልናት ፡ አለ ። ዳዊትም ፦ ወደ ፡ እነዚያ ፡ ሠራዊት ፡ ዘንድ ፡ ልትመራኝ ፡ ትወድዳለህን ? አለው ፤ እርሱም ፦ እንዳትገድለኝ ፥ ለጌታዬም ፡ እጅ ፡ አሳልፈህ ፡ እንዳትሰጠኝ ፡ በአምላክ ፡ ማልልኝ ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ እነዚያ ፡ ሠራዊት ፡ እመራሃለሁ ፡ አለ ።

፲፮ ወደ ፡ ታችም ፡ እንዲወርድ ፡ ባደረገው ፡ ጊዜ ፥ እነሆ ፥ ከፍልስጥኤማውያንና ፡ ከይሁዳ ፡ ምድር ፡ ከወሰዱት ፡ ከብዙ ፡ ምርኮ ፡ ሁሉ ፡ የተነሣ ፡ በልተው ፡ ጠጥተውም ፡ የበዓልም ፡ ቀን ፡ አድርገው ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ተበትነው ፡ ነበር ።
፲፯ ዳዊትም ፡ ከማታ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ማግሥቱ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ መታቸው ፤ ከእነርሱም ፡ በግመል ፡ ተቀምጠው ፡ ከሸሹ ፡ ከአራት ፡ መቶ ፡ ጕልማ
፲፰ ሶች ፡ በቀር ፡ አንድ ፡ ያመለጠ ፡ የለም ። ዳዊትም ፡ አማሌቃውያን ፡ የወሰዱትን ፡ ሁሉ ፡ አስ
፲፱ ጣላቸው ፥ ሁለቱንም ፡ ሚስቶቹን ፡ አዳነ ። ከወንዶችና ፡ ከሴቶች ፡ ልጆች ፥ ከወሰዱትም ፡ ምርኮ ፡ ሁሉ ፥ ታላቅም ፡ ሆነ ፡ ታናሽም ፡ ሆነ ፥ ምንም ፡ የጐደለባቸው ፡ የለም ፤ ዳዊትም ፡
፳ ሁሉን ፡ አስጣለ ። ዳዊትም ፡ የበጉንና ፡ የላሙን ፡ መንጋ ፡ ሁሉ ፡ ወሰደ ፥ ከራሱም ፡ ከብት ፡ ፊት ፡ እየነዳ ፦ ይህ ፡ የዳዊት ፡ ምርኮ ፡ ነው ፡ አለ ።

፳፩ ዳዊትም ፡ ደክመው ፡ ዳዊትን ፡ ይከተሉት ፡ ዘንድ ፡ ወዳልቻሉ ፥ በባሦር ፡ ወንዝ ፡ ወዳስቀራቸው ፡ ወደ ፡ ሁለቱ ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ መጣ ፤ እነርሱም ፡ ዳዊትን ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩትን ፡ ሕዝብ ፡ ሊቀበሉ ፡ ወጡ ፤ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፡ ደኅንነታቸውን ፡ ጠየቀ ።
፳፪ ከዳዊትም ፡ ጋር ፡ ከሄዱ ፡ ሰዎች ፡ ክፉዎቹና ፡ ምናምንቴዎቹ ፡ ሁሉ ፦ እነዚህ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ አልመጡምና ፡ እየራሳቸው ፡ ሚስቶቻቸውንና ፡ ልጆቻቸውን ፡ ይዘው ፡ ይሂዱ ፡ እንጂ ፡ ካስጣልነው ፡ ምርኮ ፡ ምንም ፡ አንሰጣቸውም ፡
፳፫ አሉ ። ዳዊትም ፦ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፥ የጠበቀን ፡ በእኛም ፡ ላይ ፡ የመጣውን ፡ ጭፍራ ፡ በእጃችን ፡ አሳልፎ ፡ የሰጠን ፡ እግዚአብሔር ፡ በሰ
፳፬ ጠን ፡ ነገር ፡ እንዲህ ፡ አታድርጉ ፤ ይህንስ ፡ ነገር ፡

ማን ፡ ይሰማችኋል ? ነገር ፡ ግን ፡ የተዋጉትና ፡ ዕቃውን ፡ የጠበቁት ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ እኩል ፡ ፳፭ ይሆናል ፥ እንድነት ፡ ይከፈላሉ ፡ አለ ። ከዚያም ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ይህን ፡ ለእስራኤል ፡ ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ አደረገው ።

፳፮ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ ጺቅላግ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ለዘመዶቹ ፡ ለይሁዳ ፡ ሽማግሌዎች ፡— እነሆ ፥ ከእግዚአብሔር ፡ ጠላቶች ፡ ምርኮ ፡ በረከትን ፡ ተቀበሉ ፡ ብሎ ፡ ከምርኮው ፡ ሰደደላቸው ። ፳፯ በቤቴል ፡ ለነበሩ ፥ በራሞት ፡ በደቡብ ፡ ለነ ፳፰ በሩ ፥ በየቲር ፡ ለነበሩ ፥ በአሮዔር ፡ ለነበሩ ፥ በሢፍሞት ፡ ለነበሩ ፥ በኤሽትሞዓ ፡ ለነበሩ ፥ ፳፱ በቀርሜሎስ ፡ ለነበሩ ፥ በይረሕምኤላውያንና ፡ ፴ በቄናውያን ፡ ከተሞችም ፡ ለነበሩ ፥ በሔርማ ፡ ለነበሩ ፥ በቦራሣን ፡ ለነበሩ ፥ በዓታክ ፡ ለነበሩ ፥ ፴፩ በኬብሮን ፡ ለነበሩ ፥ ዳዊትና ፡ ሰዎቹም ፡ በተመላለሱበት ፡ ስፍራ ፡ ለነበሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ላከ ።

ምዕራፍ ፡ ፴፩ ።

፩ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ከእስራኤል ፡ ጋር ፡ ተዋጉ ፤ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ ፊት ፡ ሸሹ ፥ ተወግተውም ፡ በጊልቦዓ ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ወደቁ ። ፪ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ሳኦልንና ፡ ልጆቹን ፡ በእግር ፡ በእግራቸው ፡ ተከትለው ፡ አባረሩአቸው ፤ ፍልስጥኤማውያንም ፡ የሳኦልን ፡ ልጆች ፡ ዮናታንንና ፡ አሚናዳብን ፡ ሜልኪሳንም ፡ ገደሉ ። ፫ ሰልፍም ፡ በሳኦል ፡ ላይ ፡ ጠነከረ ፥ ቀስተኞችም ፡ አገኙት ፤ እርሱም ፡ ከቀስተኞቹ ፡ የተነሣ ፡ እጅግ ፡ ተጨነቀ ። ፬ ሳኦልም ፡ ጋሻ ፡ ጃግሬውን ፡— እነዚህ ፡ ቈላፋን ፡ መጥተው ፡ እንዳይወጉኝና ፡ እንዳይሳለቁብኝ ፡ ሰይፍህን ፡ መዝዘህ ፡ ውጋኝ ፡ አለው ። ጋሻ ፡ ጃግሬው ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ፈርቶ ፡ ነበርና ፡ እንቢ ፡ አለ ። ሳኦልም ፡ ሰይፉን ፡ ወስዶ ፡ በላዩ ፡ ወደቀ ። ፭ ጋሻ ፡ ጃግሬውም ፡ ሳኦል ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ በሰይፉ ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ሞተ ። ፮ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሳኦል ፡ ሦስቱም ፡ ልጆቹ ፡ ጋሻ ፡ ጃግሬውም ፡ ሰዎቹም ፡ ሁሉ ፡ በአንድ ፡ ላይ ፡ ሞቱ ።

፯ በሸለቆውም ፡ ማዶና ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ የነበሩ ፡ እስራኤላውያን ፡ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ሸሹ ፥ ሳኦልና ፡ ልጆቹም ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ ከተሞቹን ፡ ለቅቀው ፡ ሸሹ ፤ ፍልስጥኤማውያንም ፡ መጥተው ፡ ተቀመጡባቸው ። ፰ በማግሥቱም ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ የሞቱትን ፡ ለመግፈፍ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ሳኦልና ፡ ሦስቱ ፡ ልጆቹ ፡ በጊልቦዓ ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ወድቀው ፡ አገኙአቸው ። ፱ የሳኦልንም ፡ ራስ ፡ ቈርጠው ፡ የጦር ፡ ዕቃውን ፡ ገፍፈው ፡ ለጣዖታቱ ፡ መቅደስ ፡ ለሕዝቡም ፡ የምስራች ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ሰደዱ ። ፲ የጦር ፡ ዕቃውንም ፡ በአስታሮት ፡ መቅደስ ፡ ውስጥ ፡ አኖሩት ፤ ሬሳውንም ፡ በቤትሳን ፡ ቅጥር ፡ ላይ ፡ አንጠለጠሉት ። ፲፩ ፍልስጥኤማውያንም ፡ በሳኦል ፡ ላይ ፡ ያደረጉትን ፡ የኢያቢስ ፡ ገለዓድ ፡ ሰዎች ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፥ ፲፪ ጀግኖች ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ተነሥተው ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ ሄዱ ፥ የሳኦልንም ፡ ሬሳ ፡ የልጆቹንም ፡ ሬሳ ፡ ከቤትሳን ፡ ቅጥር ፡ ላይ ፡ አወረዱ ፤ ወደ ፡ ኢያቢስም ፡ መጡ ፥ በዚያም ፡ አቃጠሉት ። ፲፫ አጥንታቸውንም ፡ ወሰዱ ፡ በኢያቢስም ፡ ባለው ፡ በአጣጡ ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ ቀበሩት ፥ ሰባት ፡ ቀንም ፡ ጾሙ ።

# መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልእ ።

( እርሱም ፡ መጽሐፈ ፡ ነገሥት ፡ ካልእ ፡ ነው ። )

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፥ ሳኦል ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ዳዊት ፡ አማሌቃውያንን ፡ ከመግደል ፡ ተመልሶ ፡ በጺቅላግ ፡ ሁለት ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ ተቀመጠ ። ፪ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፥ እነሆ ፥ ከሳኦል ፡ ሰፈር ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ልብሱን ፡ ቀድዶ ፡ በራሱም ፡ ላይ ፡ ትቢያ ፡ ነስንሶ ፡ መጣ ፤ ወደ ፡ ዳዊትም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ በግምበሩ ፡ ተደፍቶ ፡ እጅ ፡ ነሣ ። ፫ ዳዊትም ፡— ከወዴት ፡ መጣህ ? አለው ፤ እርሱም ፡— ከእስራኤል ፡ ሰፈር ፡ ኰብልዬ ፡ መጣሁ ፡ ፬ አለው ። ዳዊትም ፡— ነገሩ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ሆነ ? እስኪ ፡ ንገረኝ ፡ አለው ። እርሱም ፡ መልሶ ፡— ሕዝቡ ፡ ከሰልፉ ፡ ሸሽቶአል ፥ ከሕዝቡ ፡ ብዙው ፡ ወደቀ ፡ ሞቱም ፤ ሳኦልና ፡ ልጁም ፡ ዮናታን ፡ ደግሞ ፡ ሞተዋል ፡ አለ ። ፭ ዳዊትም ፡ ወሬኛውን ፡ ጐልማሳ ፡— ሳኦልና ፡ ልጁ ፡ ዮናታን ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡ በምን ፡ ታውቃለህ ? አለው ። ፮ ወሬኛውም ፡ ጐልማሳ ፡ አለ ፡— በድንገት ፡ ወደ ፡ ጊልቦዓ ፡ ተራራ ፡ መጣሁ ፥ እነሆም ፥ ሳኦል ፡ ጦሩን ፡ ተመርኵዞ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፤ ሰረገሎችና ፡ ፈረሰኞችም ፡ ተከትለው ፡ ደረሱበት ። ፯ ወደ ፡ ኋላውም ፡ ዘወር ፡ አለና ፡ እኔን ፡ አይቶ ፡ ጠራኝ ፤ እኔም ፡— እነሆኝ ፡ አልሁ ። ፰ እርሱም ፡— አንተ ፡ ማን ፡ ነህ ? አለኝ ፤ እኔም ፡— አማሌቃዊ ፡ ነኝ ፡ ብዬ ፡ መለስሁለት ። ፱ እርሱም ፡— ሰውነቴ ፡ ዝሎአልና ፥ ደግሞ ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ ድረስ ፡ ነፍሴ ፡ ገና ፡ ፈጽማ ፡ ሕያው ፡ ናትና ፡ በላዬ ፡ ቆመህ ፡ ግደለኝ ፡ አለኝ ። ፲ እኔም ፡ ከወደቀ ፡ በኋላ ፡ አለ ፡ መዳኑን ፡ አይቼ ፡ በላዩ ፡ ቆሜ ፡ ገደልሁት ፤ በራሱም ፡ ላይ ፡ የነበረውን ፡ ዘውድ ፡ በክንዱም ፡ የነበረውን ፡ ቢተዋ ፡ ወሰድሁ ፥ ወደዚህም ፡ ወደ ፡ ጌታዬ ፡ አመጣሁት ።

፲፩ ዳዊትና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩ ፡ ሰዎች ፡ ፲፪ ሁሉ ፡ ልብሳቸውን ፡ ይዘው ፡ ቀደዱ ። በሰይፍም ፡ ወድቀዋልና ፡ ለሳኦልና ፡ ለልጁ ፡ ለዮናታን ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ ሕዝብ ፡ ለእስራኤልም ፡ ወገን ፡ እንባ ፡ እያፈሰሱ ፡ አለቀሱ ÷ እስከ ፡ ማታም ፡ ድረስ ፡ ጾሙ ። ፲፫ ዳዊትም ፡ ወሬኛውን ፡ ጐልማሳ ፡— አንተ ፡ ከወዴት ፡ ነህ ? አለው ፤ እርሱም ፡— እኔ ፡ የመጻተኛው ፡ የአማሌቃዊው ፡ ልጅ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ። ፲፬ ዳዊትም ፡— እግዚአብሔር ፡ የቀባውን ፡ ለመግደል ፡ እጅህን ፡ ፲፭ ስትዘረጋ ፡ ለምን ፡ አልፈራህም ? አለው ። ዳዊትም ፡ ከጐልማሶቹ ፡ አንዱን ፡ ጠርቶ ፡— ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀረብና ፡ ውደቅበት ፡ አለው ። እርሱም ፡ መታው ÷ ሞተም ። ፲፮ ዳዊትም ፡— እግዚአብሔር ፡ የቀባውን ፡ እኔ ፡ ገድያለሁ ፡ ብሎ ፡ አፍህ ፡ በላይህ ፡ መስክሮአልና ፡ ደምህ ፡ በራስህ ፡ ላይ ፡ ይሁን ፡ አለው ።

፲፯ ዳዊትም ፡ ስለ ፡ ሳኦልና ፡ ስለ ፡ ልጁ ፡ ስለ ፡ ፲፰ ዮናታን ፡ ይህን ፡ የኀዘን ፡ ቅኔ ፡ ተቀኘ ÷ የይሁዳንም ፡ ልጆች ፡ ያስተምሩ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ። እነሆ ÷ ይህ ፡ በያሻር ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፎአል ።

፲፱ የእስራኤል ፡ ክብር ፡ በኮረብቶች ፡ ላይ ፡ ተወግቶ ፡ ሞተ ፤
ኃያላን ፡ እንዴት ፡ ወደቁ !
፳ የፍልስጥኤማውያን ፡ ቈነጃጅት ፡ ደስ ፡ እንዳይላቸው ÷
የቈላፋንም ፡ ቈነጃጅት ፡ እልል ፡ እንዳይሉ ÷
በጌት ፡ ውስጥ ፡ አታውሩ ፤
በአስቀሎናም ፡ አደባባይ ፡ የምስራች ፡ አትበሉ ።
፳፩ እናንተ ፡ የጊልቦዓ ፡ ተራሮች ፡ ሆይ ÷
የሳኦል ፡ጋሻ ፡ በዘይት ፡ እንዳልተቀባ ÷
የኃያላን ፡ ጋሻ ፡ በዚያ ፡ ወድቆአልና ፡
ዝናብና ፡ ጠል ፡ አይውረድባችሁ ÷
ቍርባንንም ፡ የሚያበቅል ፡ እርሻ ፡ አይሁንባችሁ ።
፳፪ ከሞቱት ፡ ደምና ፡ ከኃያላን ፡ ስብ ፡
የዮናታን ፡ ቀስት ፡ አልተመለሰችም ÷
የሳኦልም ፡ ሰይፍ ፡ በከንቱ ፡ አልተመለሰም ።
፳፫ ሳኦልና ፡ ዮናታን ፡ የተዋደዱና ፡ የተስማሙ ፡ ነበሩ ፤
በሕይወታቸውና ፡ በሞታቸው ፡ አልተለያዩም ፤
ከንስር ፡ ይልቅ ፡ ፈጣኖች ፡ ነበሩ ፤
ከአንበሳም ፡ ይልቅ ፡ ብርቱዎች ፡ ነበሩ ።
፳፬ የእስራኤል ፡ ቈነጃጅት ፡ ሆይ ÷
ቀይ ፡ ሐርና ፡ ጥሩ ፡ ግምጃ ፡ ያለብሳችሁ ፡ ለነበረ ÷
በወርቀዘቦም ፡ ላስጌጣችሁ ፡ ለሳኦል ፡ አልቅሱለት ።
፳፭ ኃያላንም ፡ በሰልፍ ፡ ውስጥ ፡ እንዴት ፡ ወደቁ !
ዮናታንም ፡ በኮረብቶችህ ፡ ላይ ፡ ወድቆአል ።
፳፮ ወንድሜ ፡ ዮናታን ፡ ሆይ ÷ እኔ ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ እጨነቃለሁ ፤
በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ውድህ ፡ እጅግ ፡ የተለየ ፡ ነበረ ፤
ከሴት ፡ ፍቅር ፡ ይልቅ ፡ ፍቅርህ ፡ ለእኔ ፡ ግሩም ፡ ነበረ ።
፳፯ ኃያላን ፡ እንዴት ፡ ወደቁ !
የሰልፍም ፡ ዕቃ ፡ እንዴት ፡ ጠፋ !

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ዳዊት ፡— ከይሁዳ ፡ ከተሞች ፡ ወደ ፡ አንዲቱ ፡ ልውጣን ? ብሎ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠየቀ ። እግዚአብሔርም ፡— ውጣ ፡ አለው ። ዳዊትም ፡— ወዴት ፡ ልውጣ ? አለ ። እርሱም ፡— ወደ ፡ ኬብሮን ፡ ውጣ ፡ አለው ። ፪ ዳዊትም ፡ ከሁለቱ ፡ ሚስቶቹ ፡ ከኢይዝራኤላዊቱ ፡ ከአኪናሆምና ፡ የቀርሜሎሳዊው ፡ የናባል ፡ ሚስት ፡ ከነበረችው ፡ ከአቢግያ ፡ ጋር ፡ ወደዚያ ፡ ወጣ ። ፫ ዳዊትም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩትን ፡ ሰዎችና ፡ ቤት ፡ ሰባቸውን ፡ ሁሉ ፡ አመጣ ፤ በኬብሮንም ፡ ከተሞች ፡ ተቀመጡ ። ፬ የይሁዳም ፡ ሰዎች ፡ መጥተው ፡ በይሁዳ ፡ ቤት ፡ ይነግሥ ፡ ዘንድ ፡ ዳዊትን ፡ በዚያ ፡ ቀቡት ።

ሳኦልን ፡ የቀበሩት ፡ የኢያቢስ ፡ ገለዓድ ፡ ሰዎች ፡ ናቸው ፡ ብለው ፡ ለዳዊት ፡ ነገሩት ። ፭ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ ኢያቢስ ፡ ገለዓድ ፡ ሰዎች ፡ መልእክተኞችን ፡ ልኮ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— እናንተ ፡ ለጌታችሁ ፡ ለሳኦል ፡ ይህን ፡ ቸርነት ፡ አድርጋችኋልና ÷ ቀብራችሁትማልና ፡ በእግዚአብሔር ፡ የተባረካችሁ ፡ ሁኑ ። ፮ አሁንም ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸርነትንና ፡ እውነትን ፡ ያድርግላችሁ ፤ ይህንም ፡ ነገር ፡ አድርጋችኋልና ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ ይህን ፡ ቸርነት ፡ እመልስላችኋለሁ ። ፯ አሁንም ፡ ጌታችሁ ፡ ሳኦል ፡ ሞቶአልና ፡ እጃችሁ ፡ ትጽና ÷ እናንተም ፡ ጨክኑ ፤ ዳግም ፡ የይሁዳ ፡ ቤት ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ ቀብተውኛል ።

፰ የሳኦልም ፡ ጭፍራ ፡ አለቃ ፡ የኔር ፡ ልጅ ፡ አበኔር ፡ የሳኦልን ፡ ልጅ ፡ ኢያቡስቴን ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ መሃናይም ፡ አሻገረው ፤ ፱ በገለዓድና ፡ በአሹራውያን ፡ በኢይዝራኤልም ፡ በኤፍሬምም ፡ በብንያምም ፡ በእስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አነገሠው ። ፲ የሳኦል ፡ ልጅ ፡ ኢያቡስቴም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የአርባ ፡ ዓመት ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ሁለት ፡ ዓመትም ፡ ነገሠ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የይሁዳ ፡ ቤት ፡ ዳዊትን ፡ ተከተለ ። ፲፩ ዳዊትም ፡ በይሁዳ ፡ ቤት ፡ ነግሦ ፡ በኬብሮን ፡ የተቀመጠበት ፡ ዘመን ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ከስድስት ፡ ወር ፡ ነበረ ።

፲፪ የኔር ፡ ልጅ ፡ አበኔርና ፡ የሳኦል ፡ ልጅ ፡ የኢያቡስቴ ፡ ብላቴኖች ፡ ከመሃናይም ፡ ወደ ፡ ገባዖን ፡ ወጡ ። ፲፫ የጽሩያ ፡ ልጅ ፡ ኢዮአብና ፡ የዳ

ዊት ፡ ባሪያዎች ፡ ወጥተው ፡ በገባዖን ፡ ውኃ ፡ መቆሚያ ፡ አጠገብ ፡ ተገናኙአቸው ፤ በውኃውም ፡ መቆሚያ ፡ በአንዱ ፡ ወገን ፡ እነዚህ ÷ በሌላውም ፡ ወገን ፡ እነዚያ ፡ ሆነው ፡ ተቀመጡ ።

፲፬ አበኔርም ፡ ኢዮአብን ፦ ጕልማሶች ፡ ይነሡ ÷ በፊታችንም ፡ ይቈራቈሱ ፡ አለው ፤ ኢዮአብም ፦ ይነሡ ፡ አለ ። ፲፭ ለብንያም ፡ ወገንና ፡ ለሳኦል ፡ ልጅ ፡ ለኢያቡስቴ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ÷ ከዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ተቈጥረው ፡ ተነሡ ። ፲፮ ሁሉም ፡ እያንዳንዱ ፡ የወደረኛውን ፡ ራስ ፡ ያዘ ÷ ሰይፉንም ፡ በወደረኛው ፡ ጐን ፡ ሻጠ ÷ ተያይዘውም ፡ ወደቁ ። የዚያም ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ የስለታም ፡ ሰይፍ ፡ እርሻ ፡ ተብሎ ፡ ተጠራ ÷ እርሱም ፡ በገባዖን ፡ ነው ። ፲፯ በዚያም ፡ ቀን ፡ ጽኑ ፡ ሰልፍ ፡ ሆነ ፤ በዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡ ፊት ፡ አበኔርና ፡ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ተሸነፉ ።

፲፰ በዚያም ፡ ሦስቱ ፡ የጽሩያ ፡ ልጆች ፡ ኢዮአብና ፡ አቢሳ ፡ አሣሄልም ፡ ነበሩ ፤ አሣሄልም ፡ እንደ ፡ ዱር ፡ ሚዳቋ ፡ በሩጫ ፡ ፈጣን ፡ ነበረ ። ፲፱ አሣሄልም ፡ የአበኔርን ፡ ፍለጋ ፡ ተከታተለ ÷ አበኔርንም ፡ ከማሳደድ ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ አላለም ። ፳ አበኔርም ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ተመለከተና ፦ አንተ ፡ አሣሄል ፡ ነህን ? አለ ። እርሱም ፦ እኔ ፡ ነኝ ፡ አለ ። ፳፩ አበኔርም ፦ ወደ ፡ ቀኝ ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ ግራ ፡ ፈቀቅ ፡ በል ፤ አንድ ፡ ጕልማሳ ፡ ያዝ ÷ መሣርያውንም ፡ ውሰድ ፡ አለው ። አሣሄል ፡ ግን ፡ እርሱን ፡ ከማሳደድ ፡ ፈቀቅ ፡ ይል ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ አለ ። ፳፪ አበኔርም ፡ አሣሄልን ፦ ከምድር ፡ ጋር ፡ እንዳላጣብቅህ ፡ እኔን ፡ ከማሳደድ ፡ ፈቀቅ ፡ በል ፤ ወደ ፡ ወንድምህ ፡ ወደ ፡ ኢዮአብ ፡ ፊቴን ፡ አቅንቼ ፡ አይ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ይቻለኛል ? አለው ። ፳፫ ነገር ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ ፈቀቅ ፡ ይል ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ አለ ፤ አበኔርም ፡ በጦሩ ፡ ጫፍ ፡ ሆዱን ፡ ወጋው ÷ ጦሩም ፡ በኋላው ፡ ወጣ ÷ በዚያም ፡ ስፍራ ፡ ወድቆ ፡ ሞተ ። አሣሄልም ፡ ወድቆ ፡ በሞተበቱ ፡ ስፍራ ፡ የሚያልፍ ፡ ሁሉ ፡ ይቆም ፡ ነበር ።

፳፬ ኢዮአብና ፡ አቢሳም ፡ አበኔርን ፡ አሳደዱ ፤ በገባዖንም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ መንገድ ፡ በጋይ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ እስካለው ፡ እስከ ፡ አማ ፡ ኮረብታ ፡ ድረስ ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፡ ፀሐይ ፡ ጠለቀች ። ፳፭ የብንያምም ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ አበኔር ፡ ተሰበሰቡ ÷ በአንድነትም ፡ ሆኑ ÷ በኮረብታም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ቆሙ ። ፳፮ አበኔርም ፡ ወደ ፡ ኢዮአብ ፡ ጮኸ ፦ ሰይፍ ፡ በውኑ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ያጠፋልን ? ፍጻሜውሳ ፡ መራራ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አታውቅምን ? ሕዝቡ ፡ ወንድሞቻቸውን ፡ ከማሳደድ ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝቡን ፡ የማትናገር ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ? አለው ። ፳፯ ኢዮአብም ፦ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! በትናገር ፡ ኖሮ ፡ ሕዝቡ ፡ በጥዋት ፡ ወጥተው ፡ በሄዱ ፡ ነበር ÷ ወንድሞቻቸውንም ፡ ማሳደድ ፡ በተዉ ፡ ነበር ፡ አለ ። ፳፰ ኢዮአብም ፡ ቀንደ ፡ መለከት ፡ ነፋ ÷ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ቆመ ÷ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እስራኤልን ፡ አላሳደደም ÷ ሰልፍም ፡ አላደረገም ። ፳፱ አበኔርና ፡ ሰዎቹም ፡ ሌሊቱን ሁሉ ፡ ዓረብ ፡ እያለፉ ፡ ሄዱ ፤ ዮርዳኖስንም ፡ ተሻገሩ ÷ ቢትሮንንም ፡ ሁሉ ፡ ከለፉ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ መሃናይም ፡ መጡ ።

፴ ኢዮአብም ፡ አበኔርን ፡ ከማሳደድ ፡ ተመለሰ ፤ ሕዝቡንም ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰበ ÷ ከዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡ ከአሣሄል ፡ ሌላ ፡ አሥራ ፡ ዘጠኝ ፡ ሰዎች ፡ ጐደሉ ። ፴፩ የዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡ ከብንያምና ፡ ከአበኔር ፡ ሰዎች ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ ያህል ፡ ገደሉ ። ፴፪ አሣሄልንም ፡ አንሥተው ፡ በቤተ ፡ ልሔም ፡ በአባቱ ፡ መቃብር ፡ ቀበሩት ፤ ኢዮአብና ፡ ሰዎቹም ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ ሄዱ ÷ በኬብሮንም ፡ አነጉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ በሳኦል ፡ ቤትና ፡ በዳዊት ፡ ቤት ፡ መካከል ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ጦርነት ፡ ሆነ ፤ የዳዊት ፡ ቤት ፡ እየበረታ ÷ የሳኦል ፡ ቤት ፡ ግን ፡ እየደከመ ፡ የሚሄድ ፡ ሆነ ።

፪ ለዳዊትም ፡ ወንድ ፡ ልጆች ፡ በኬብሮን ፡ ተወለዱለት ፤ በኵሩም ፡ ከኢይዝራኤላዊቱ ፡ ከአኪናሆም ፡ የተወለደው ፡ አምኖን ፡ ነበረ ። ፫ ሁለተኛውም ፡ የቀርሜሎሳዊው ፡ የናባል ፡ ሚስት ፡ ከነበረች ፡ ከአቢግያ ፡ የተወለደው ፡ ዶሎሕያ ፡ ነበረ ። ሦስተኛውም ፡ ከጌሹር ፡ ንጉሥ ፡ ከተልማይ ፡ ልጅ ፡ ከመዓካ ፡ የተወለደው ፡ አቤሴሎም ፡ ነበረ ። ፬ አራተኛውም ፡ የአጊት ፡ ልጅ ፡ አዶንያስ ÷ አምስተኛውም ፡ የአቢጣል ፡ ልጅ ፡ ሰፋጥያስ ፡ ነበረ ። ፭ ስድስተኛውም ፡ የዳዊት ፡ ሚስት ፡ የዔግላ ፡ ልጅ ፡ ይትረኃም ፡ ነበረ ። እነዚህም ፡ ለዳዊት ፡ በኬብሮን ፡ ተወለዱለት ።

፮ በሳኦል ፡ ቤትና ፡ በዳዊት ፡ ቤት ፡ መካከል ፡ ጦርነት ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ አበኔር ፡ በሳኦል ፡ ቤት ፡ ይበረታ ፡ ነበር ። ፯ ለሳኦልም ፡ የኢዮሄል ፡ ልጅ ፡ ሪጽፋ ፡ የተባለች ፡ ቁባት ፡ ነበረችው ፤ ኢያቡስቴም ፡ አበኔርን ፦ ወደ ፡ አባቴ ፡ ቁባት ፡ ለምን ፡ ገባህ ? አለው ። ፰ አበኔርም ፡ በኢያቡስቴ ፡ ቃል ፡ እጅግ ፡ ተቈጥቶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ እኔ ፡ ለአባትህ ፡ ለሳኦል ፡ ቤት ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለዘመዶቹም ፡ ቸርነት ፡ አድርጌአለሁ ÷ አንተንም ፡ ለዳዊት ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ አልሰጠሁም ፤ አንተም ፡ ዛሬ ፡ ከዚህች ፡ ሴት ፡ ጋር ፡ ስለ ፡ ሠራሁት ፡ ኃጢአት ፡ ትከስሰኛለህ ፤ በውኑ ፡ እኔ ፡ የውሻ ፡ ራስ ፡ ነኝን ? ፱፡፲ መንግሥትን ፡ ከሳኦል ፡ ቤት ፡ ያወጣ ፡ ዘንድ ፡ የዳዊትንም ፡ ዙፋን ፡ በእስራኤልና ፡ በይሁዳ ፡ ከዳን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ቤርሳቤህ ፡ ድረስ ፡ ከፍ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዳዊት ፡ እንደ ፡ ማለለት ፡ እንዲሁ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ባላደርግ ፡ እግዚአብሔር ፡ በአበኔር ፡ ይህን ፡ ያድርግበት ፡ ይህንም ፡ ይጨምርበት ። ፲፩ ኢያቡስቴም ፡ አበኔርን ፡ ይፈራው ፡ ነበርና ፡ አንዳች ፡ ይመልስለት ፡ ዘንድ ፡ አልቻለም ።

፲፪ አበኔርም ፡ ለዳዊት ፦ ምድሪቱ ፡ ለማን ፡ ናት ? ከእኔ ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አድርግ ÷

እጅም፡ ከአንተ፡ ጋር፡ ትሆናለች ፥ እስራኤልንም፡ ሁሉ፡ ወደ፡ አንተ፡ እመልሰዋለሁ፡ ብለው፡ ይነግሩት፡ ዘንድ፡ መልእክተኞች፡ ሰደደለት ። ፲፫ ዳዊትም፡— ይሁን፥ ከአንተ፡ ጋር፡ ቃል፡ ኪዳን፡ አደርጋለሁ ፤ ነገር፡ ግን፡ አንድ፡ ነገር፡ ከአንተ፡ እሻለሁ ፤ ፊቴን፡ ለማየት፡ በመጣህ፡ ጊዜ፥ የሳኦልን፡ ልጅ፡ ሜልኮልን፡ ካላመጣህልኝ፡ ፊቴን፡ አታይም፡ አለ ። ፲፬ ዳዊትም፡ ወደ፡ ሳኦል፡ ልጅ፡ ወደ፡ ኢያቡስቴ፡— በመቶ፡ ፍልስጥኤማውያን፡ ሸለፈት፡ ያጨኋትን፡ ሚስቴን፡ ሜልኮልን፡ ስጠኝ፡ ብሎ፡ መልእክተኞችን፡ ሰደደ ። ፲፭ ኢያቡስቴም፡ ልኮ፡ ከሌሳ፡ ልጅ፡ ከባልዋ፡ ከፈልጢኤል፡ ወሰዳት ። ፲፮ ባልዋም፡ እያለቀሰ፡ ከእርስዋ፡ ጋር፡ ሄደ፥ እስከ፡ ብራቂም፡ ድረስ፡ ተከተላት ። አበኔርም፡— ሂድ፥ ተመለስ፡ አለው ፤ እርሱም፡ ተመለሰ ።

፲፯ አበኔርም፡ ለእስራኤል፡ ሽማግሌዎች፡— አስቀድሞ፡ ዳዊት፡ በእናንተ፡ ላይ፡ ንጉሥ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ፈልጋችሁ፡ ነበር ። ፲፰ እግዚአብሔርም፡ ስለ፡ ዳዊት፡— በባሪያዬ፡ በዳዊት፡ እጅ፡ ሕዝቤን፡ እስራኤልን፡ ከፍልስጥኤማውያን፡ እጅና፡ ከጠላቶቻቸው፡ ሁሉ፡ እጅ፡ አድናለሁ፡ ብሎ፡ ተናግሮአልና፡ እንግዲህ፡ አሁን፡ አድርጉ፡ ብሎ፡ ነገራቸው ። ፲፱ አበኔርም፡ ደግሞ፡ በብንያም፡ ወገን፡ ጆሮ፡ ተናገረ ፤ አበኔርም፡ ደግሞ፡ በእስራኤልና፡ በብንያም፡ ቤት፡ ሁሉ፡ መልካም፡ የነበረውን፡ ለዳዊት፡ ሊነግረው፡ ወደ፡ ኬብሮን፡ ሄደ ። ፳ አበኔርም፡ ከሀያ፡ ሰዎች፡ ጋር፡ ወደ፡ ዳዊት፡ ወደ፡ ኬብሮን፡ መጣ ። ዳዊትም፡ ለአበኔርና፡ ከእርሱ፡ ጋር፡ ለነበሩት፡ ሰዎች፡ ግብዣ፡ አደረገላቸው ። ፳፩ አበኔርም፡ ዳዊትን፡— ተነሥቼ፡ ልሂድ፥ ከአንተ፡ ጋርም፡ ቃል፡ ኪዳን፡ እንዲያደርጉ፥ ነፍስህም፡ እንደ፡ ወደደች፡ ሁሉን፡ እንድትገዛ፡ እስራኤልን፡ ሁሉ፡ ለጌታዬ፡ ለንጉሥ፡ ልሰብስብ፡ አለው ። ዳዊትም፡ አበኔርን፡ አሰናበተው፥ በደኅናም፡ ሄደ ።

፳፪ በዚያን፡ ጊዜም፡ የዳዊት፡ ባሪያዎችና፡ ኢዮአብ፡ ከዘመቻ፡ ታላቅ፡ ምርኮ፡ ይዘው፡ መጡ ። አበኔር፡ ግን፡ ዳዊት፡ አሰናብቶት፡ በደኅና፡ ሄዶ፡ ነበር፡ እንጂ፡ በኬብሮን፡ አልነበረም ። ፳፫ ኢዮአብና፡ ከእርሱም፡ ጋር፡ የነበረ፡ ጭፍራ፡ ሁሉ፡ በመጡ፡ ጊዜ፡— የኔር፡ ልጅ፡ አበኔር፡ ወደ፡ ንጉሥ፡ መጣ፥ አሰናበተውም፡ በደኅናውም፡ ሄደ፡ ብለው፡ ሰዎች፡ ለኢዮአብ፡ ነገሩት ። ፳፬ ኢዮአብም፡ ወደ፡ ንጉሥ፡ ገብቶ፡— ምን፡ አደረግህ ? እነሆ፥ አበኔር፡ መጥቶልህ፡ ነበር ፤ በደኅና፡ እንዲሄድ፡ ስለ፡ ምን፡ አሰናበትኸው ? ፳፭ የኔር፡ ልጅ፡ አበኔር፡ ያታልልህ፡ ዘንድ፥ መውጫህንና፡ መግቢያህንም፡ ያውቅ፡ ዘንድ፥ የምታደርገውንም፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ያስተውል፡ ዘንድ፡ እንደ፡ መጣ፡ አታውቅምን ? አለው ። ፳፮ ኢዮአብም፡ ከዳዊት፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ መልእክተኞችን፡ ከአበኔር፡ በኋላ፡ ላከ፥ ከሴይርም፡ ጉድጓድም፡ መለሱት ። ዳዊት፡ ግን፡ ይህን፡ አላወቀም ።

፳፯ አበኔርም፡ ወደ፡ ኬብሮን፡ በተመለሰ፡ ጊዜ፡ ኢዮአብ፡ በበር፡ ውስጥ፡ በቈይታ፡ ይናገረው፡ ዘንድ፡ ወደ፡ አጠገቡ፡ ወሰደው ፤ በዚያም፡ ለወንድሙ፡ ለአሣሄል፡ ደም፡ ተበቅሎ፡ ሆዱን፡ መታው፥ ሞተም ። ፳፰ በኋላም፡ ዳዊት፡ ይህ፡ ነገር፡ እንደ፡ ተደረገ፡ በሰማ፡ ጊዜ፡— ከኔር፡ ልጅ፡ ከአበኔር፡ ደም፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ለዘላለም፡ እኔ፡ ንጹሕ፡ ነኝ፥ መንግሥቴም፡ ንጹሕ፡ ነው ፤ ፳፱ በኢዮአብ፡ ራስ፡ ላይና፡ በአባቱ፡ ቤት፡ ሁሉ፡ ላይ፡ ይምጣበት ፤ በኢዮአብም፡ ቤት፡ ፈሳሽ፡ ነገር፡ ያለበት፡ ወይም፡ ለምጻም፡ ወይም፡ አንካሳ፡ ወይም፡ በሰይፍ፡ የሚወድቅ፡ ወይም፡ እንጀራ፡ የሌለው፡ ሰው፡ አይታጣ፡ አለ ። ፴ ኢዮአብና፡ ወንድሙ፡ አቢሳም፡ በሰልፍ፡ በገባዖን፡ ወንድማቸውን፡ አሣሄልን፡ ገድሎ፡ ነበርና፡ አበኔርን፡ ገደሉት ።

፴፩ ዳዊትም፡ ኢዮአብንና፡ ከእርሱ፡ ጋር፡ የነበሩትን፡ ሕዝብ፡ ሁሉ፡— ልብሳችሁን፡ ቀደዱ፥ ማቅም፡ ልበሱ፥ በአበኔርም፡ ፊት፡ አልቅሱ፡ አላቸው ። ንጉሡም፡ ዳዊት፡ ከቃሬዛው፡ በኋላ፡ ሄደ ። ፴፪ አበኔርንም፡ በኬብሮን፡ ቀበሩት ፤ ንጉሡም፡ ድምፁን፡ ከፍ፡ አድርጎ፡ በአበኔር፡ መቃብር፡ አጠገብ፡ አለቀሰ ፤ ሕዝቡም፡ ሁሉ፡ አለቀሱ ። ፴፫ ንጉሡም፡ ለአበኔር፡—

አበኔር፡ ሰነፍ፡ እንደሚሞት፡ ይሞታልን ?
፴፬ እጅህ፡ አልታሰረም፥ እግርህም፡ በሰንሰለት፡ አልተያዘም ፤
ሰው፡ በዓመፀኞች፡ ፊት፡ እንደሚወድቅ፡
አንተ፡ እንዲሁ፡ ወደቅህ፡

ብሎ፡ የልቅሶ፡ ቅኔ፡ ተቀኘለት ። ሕዝቡም፡ ሁሉ፡ ዋይታ፡ አብዝተው፡ አለቀሱ ። ፴፭ ሕዝቡም፡ ሁሉ፡ ገና፡ ሳይመሽ፡ ዳዊትን፡ እንጀራ፡ ይበላ፡ ዘንድ፡ ሊጋብዙት፡ መጡ ፤ ዳዊት፡ ግን፡— ፀሐይ፡ ሳትጠልቅ፡ እንጀራ፡ ወይም፡ ሌላ፡ ነገር፡ ብቀምስ፡ እግዚአብሔር፡ ይህን፡ ያድርግብኝ፥ ይህንም፡ ይጨምርብኝ፡ ብሎ ፤ ማለ ። ፴፮ ሕዝቡም፡ ሁሉ፡ ይህን፡ ተመለከቱ፥ ደስ፡ አሰኛቸውም ፤ በሕዝቡም፡ ሁሉ፡ ፊት፡ ንጉሥ፡ ያደረገው፡ ሁሉ፡ ደስ፡ አሰኛቸው ።

፴፯ በዚያም፡ ቀን፡ ሕዝቡ፡ ሁሉ፡ እስራኤልም፡ ሁሉ፡ የኔር፡ ልጅ፡ የአበኔር፡ ሞት፡ ከንጉሡ፡ ዘንድ፡ እንዳልሆነ፡ አወቁ ። ፴፰ ንጉሡም፡ ባሪያዎቹን፡— ዛሬ፡ በእስራኤል፡ ዘንድ፡ መኰንንና፡ ታላቅ፡ ሰው፡ እንደ፡ ወደቀ፡ አታውቁምን ? ፴፱ እኔም፡ ዛሬ፡ ምንም፡ ለመንገሥ፡ የተቀባሁ፡ ብሆን፡ ደካማ፡ ነኝ ፤ እነዚህም፡ ሰዎች፡ የጽሩያ፡ ልጆች፡ በርትተውብኛል ፤ እግዚአብሔር፡ ክፋት፡ በሠራ፡ ላይ፡ እንደ፡ ክፋቱ፡ ይመልስበት፡ አላቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ የሳኦልም ፡ ልጅ ፡ ኢያቡስቴ ፡ አበኔር ፡ በኬብሮን ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ እጁ ፡ ደከመች ÷ እስራኤላውያንም ፡ ሁሉ ፡ ደነገጡ ። ፪ ለሳኦልም ፡ ልጅ ፡ ለኢያቡስቴ ፡ የጭፍራ ፡ አለቆች ፡ የሆኑ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ነበሩት ፤ የአንዱም ፡ ስም ፡ በዓና ÷ የሁለተኛውም ፡ ስም ፡ ሬካብ ፡ ነበረ ÷ ከብንያምም ፡ ልጆች ፡ የብኤሮታዊው ፡ የሬሞን ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ፤ ብኤሮትም ፡ ፫ ለብንያም ፡ ተቈጥራ ፡ ነበር ። ብኤሮታውያንም ፡ ወደ ፡ ጌቴም ፡ ሸሽተው ፡ ነበር ÷ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ ተጠግተው ፡ ነበር ።

፬ ለሳኦልም ፡ ልጅ ለዮናታን ፡ አንድ ፡ ሽባ ፡ የሆነ ፡ ልጅ ፡ ነበረው ። የሳኦልና ፡ የዮናታን ፡ ወሬ ፡ ከኢይዝራኤል ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ የአምስት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ÷ ሞግዚቱም ፡ አዝላው ፡ ሸሸች ፤ ፈጥናም ፡ ስትሸሽ ፡ ወድቆ ፡ ሽባ ፡ ሆነ ። ስሙም ፡ ሜምፌቦስቴ ፡ ነበረ ።

፭ የብኤሮታዊውም ፡ የሬሞን ፡ ልጆች ፡ ሬካብና ፡ በዓና ፡ ቀኑ ፡ ሲሞቅ ፡ ወደ ፡ ኢያቡስቴ ፡ ቤት ፡ መጡ ፤ እርሱም ፡ በቀትር ፡ ጊዜ ፡ በምንጣፉ ፡ ላይ ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ። ፮ በረኛይቱም ፡ ስንዴ ፡ ታበጥር ፡ ነበር ÷ አንቀላፍታም ፡ ተኝታ ፡ ነበር ፤ ሬካብና ፡ ወንድሙ ፡ በዓናም ፡ በቀስታ ፡ ገቡ ። ፯ ወደ ፡ ቤትም ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ በእልፍኙ ፡ በምንጣፉ ፡ ላይ ፡ ተኝቶ ፡ ሳለ ፡ መቱት ÷ ገደሉትም ፤ ራሱንም ፡ ቈርጠው ፡ወሰዱት ÷ በዓረባም ፡ መንገድ ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ ሄዱ ። ፰ የኢያቡስቴንም ፡ ራስ ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ መጡ ÷ ንጉሡንም ፡— ነፍስህን ፡ ይሻ ፡ የነበረው ፡ የጠላትህ ፡ የሳኦል ፡ ልጅ ፡ የኢያቡስቴ ፡ ራስ ፡ እነሆ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዛሬ ፡ ከሳኦልና ፡ ከዘሩ ፡ ለጌታችን ፡ ለንጉሥ ፡ ተበቀለለት ፡ አሉት ። ፱ ዳዊትም ፡ ለብኤሮታዊው ፡ ለሬሞን ፡ ልጆች ፡ ለሬካብና ፡ ለወንድሙ ፡ ለበዓና ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ መለሰላቸው ፡— ነፍሴን ፡ ከመከራ ፡ ሁሉ ፡ ያዳነ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! ፲ መልካም ፡ ወሬ ፡ የያዘ ፡ መስሎት ፡— እነሆ ÷ ሳኦል ፡ ሞተ ፡ ብሎ ፡ የነገረኝን ፡ የምስራቹ ፡ ዋጋ ፡ እንዲሆን ፡ ይዤ ፡ በጺቅላግ ፡ ገደልሁት ። ፲፩ ይልቁንስ ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ በምንጣፉ ፡ ላይ ፡ ንጹሑን ፡ ሰው ፡ የገደላችሁትን ፡ እናንተን ፡ ኃጢአተኞችንማ ፡ እንዴት ፡ ነዋ ? ደሙን ፡ ከእጃችሁ ፡ አልሻውምን ? ከምድርም ፡ አላጠፋችሁምን ? ፲፪ ዳዊትም ፡ ጕልማሶቹን ፡ አዘዘ ÷ ገደሉአቸውም ፤ እጃቸውንና ፡ እግራቸውን ፡ ቈርጠው ፡ በኬብሮን ፡ በውኃ ፡ መቆሚያ ፡ አጠገብ ፡ አንጠለጠሉአቸው ። የኢያቡስቴንም ፡ ራስ ፡ ወስደው ፡ በአበኔር ፡ መቃብር ፡ በኬብሮን ፡ ቀበሩት ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ የእስራኤልም ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ መጥተው ፡— እነሆ ÷ እኛ ፡ የአጥንትህ ፡ ፍላጭ ፡ የሥጋህ ፡ ቍራጭ ፡ ነን ። ፪ አስቀድሞ ፡ ሳኦል ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ እስራኤልን ፡ የምታወጣና ፡ የምታገባ ፡ አንተ ፡ ነበርህ ፤ እግዚአብሔርም ፡— አንተ ፡ ሕዝቤን ፡ እስራኤልን ፡ ትጠብቃለህ ÷ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ ትሆናለህ ፡ ብሎሀ ፡ ነበር ፡ አሉት ። ፫ የእስራኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ መጡ ፤ ንጉሡ ፡ ዳዊትም ፡ በኬብሮን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ አደረገ ፤ በእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ዳዊትን ፡ ቀቡት ። ፬ ዳዊትም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ÷ አርባ ፡ ዓመትም ፡ ነገሠ ። ፭ በኬብሮን ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ከስድስት ፡ ወር ፡ ነገሠ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉና ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ሠላሳ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ።

፮ ንጉሡና ፡ ሰዎቹም ፡ በአገሩ ፡ ውስጥ ፡ ከተቀመጡት ፡ ከኢያቡሳውያን ፡ ጋር ፡ ለመዋጋት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሄዱ ፤ እነርሱም ፡— ዳዊት ፡ ወደዚህ ፡ ሊገባ ፡ አይችልም ፡ ብለው ፡ አስበው ፡ ነበርና ፡ ዳዊትን ፡— ዕውሮችንና ፡ አንካሶችን ፡ ካላወጣህ ፡ በቀር ፡ ወደዚህ ፡ አትገባም ፡ አሉት ። ፯ ነገር ፡ ግን ፡ ዳዊት ፡ አምባይቱን ፡ ጽዮንን ፡ ያዘ ÷ እርስዋም ፡ የዳዊት ፡ ከተማ ፡ ናት ። ፰ በዚያም ፡ ቀን ፡ ዳዊት ፡— ኢያቡሳውያንን ፡ የሚመታ ፡ በውኃ ፡ መሄጃው ፡ ይውጣ ፤ የዳዊትም ፡ ነፍስ ፡ የምትጠላቸውን ፡ ዕውሮችንና ፡ አንካሶችን ፡ ያውጣ ፡ አለ ። ስለዚህም ፡ በምሳሌ ፡— ዕውርና ፡ አንካሳ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ አይግቡ ፡ ተባለ ። ፱ ዳዊትም ፡ በአምባይቱ ፡ ውስጥ ፡ ተቀመጠ ÷ የዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ብሎ ፡ ጠራት ። ዳዊትም ፡ ዙሪያዋን ፡ ከሚሎ ፡ ጀምሮ ፡ ወደ ፡ ውስጥ ፡ ቀጠራት ። ፲ ዳዊትም ፡ እየበረታ ፡ ሄደ ፤ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረ ።

፲፩ የጢሮስም ፡ ንጉሥ ፡ ኪራም ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ መልእክተኞችን ፡ የዝግባ ፡ እንጨትንም ፡ አናጢዎችንም ፡ ጠራቢዎችንም ፡ ላከ ፤ ለዳዊትም ፡ ቤት ፡ ሠሩለት ። ፲፪ ዳዊትም ፡ እግዚአብሔር ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ አድርጎ ፡ እንዳጸናው ÷ ስለ ፡ ሕዝቡ ፡ ስለ ፡ እስራኤልም ፡ መንግሥቱን ፡ ከፍ ፡ እንዳደረገ ፡ አወቀ ።

፲፫ ዳዊትም ፡ ከኬብሮን ፡ ከመጣ ፡ በኋላ ፡ ሌሎቹን ፡ ቁባቶቹንና ፡ ሚስቶቹን ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ወሰደ ፤ ለዳዊትም ፡ ደግሞ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ተወለዱለት ። ፲፬ በኢየሩሳሌምም ፡ የተ

ወለዱለት ፡ ስማቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ሳሙስ ÷ ፲፭ ሶባብ ÷ ናታን ÷ ሰሎሞን ÷ ኢያቤሐር ÷ ኤሊ ፲፮ ሱዔ ÷ ናፌቅ ÷ ያፍያ ÷ ኤሊሳማ ÷ ኤሊዳሄ ÷ ኤሊፉላት ።

፲፯ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ዳዊት ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ሆኖ ፡ እንደ ፡ ተቀባ ፡ ሰሙ ÷ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ሁሉ ፡ ዳዊትን ፡ ሊፈልጉ ፡ ወጡ ፤ ዳዊትም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ምሽጉ ፡ ፲፰ ወረደ ። ፍልስጥኤማውያንም ፡ መጥተው ፡ በራ ፲፱ ፋይም ፡ ሸለቆ ፡ ተበትነው ፡ ሰፈሩ ። ዳዊትም ፡— ወደ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ልውጣን ? በእጄስ ፡ አሳልፈህ ፡ ትሰጣቸዋለህን ? ብሎ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠየቀ ። እግዚአብሔርም ፡ ዳዊትን ፡— ፍልስጥኤማውያንን ፡ በእርግጥ ፡ በእጅህ ፡ አሳ ፳ ልፌ ፡ እሰጣቸዋለሁና ፡ ውጣ ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ ወደ ፡ በአልፐራሲም ፡ መጣ ÷ በዚያም ፡ መታቸውና ፡— ውኃ ፡ እንዲያፈርስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጠላቶቼን ፡ በፊቴ ፡ አፈረሳቸው ፡ አለ ። ስለዚህም ፡ የዚያን ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ በአል ፳፩ ፐራሲም ፡ ብሎ ፡ ጠራው ። ጣዖቶቻቸውንም ፡ በዚያ ፡ ተዉ ÷ ዳዊትና ፡ ሰዎቹም ፡ ወሰዱአቸው ።

፳፪ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ደግሞ ፡ መጡ ÷ በራ ፳፫ ፋይምም ፡ ሸለቆ ፡ ተበትነው ፡ ሰፈሩ ። ዳዊትም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠየቀ ፤ እርሱም ፡— በኋላቸው ፡ ዞረህ ፡ በሾላው ፡ ዛፍ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ፳፬ ግጠማቸው ፡ እንጂ ፡ አትውጣ ። በሾላውም ፡ ዛፍ ፡ ራስ ፡ ውስጥ ፡ የሽውሽውታ ፡ ድምፅ ፡ ስትሰማ ÷ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ የፍልስጥኤማውያንን ፡ ጭፍራ ፡ ለመምታት ፡ በፊትህ ፡ ወጥቶ ፡ ይሆናልና ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ቸኵል ፡ ፳፭ አለው ። ዳዊትም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ አደረገ ፤ ከገባዖንም ፡ እስከ ፡ ጌዝር ፡ ድረስ ፡ ፍልስጥኤማውያንን ፡ መታ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ዳዊትም ፡ ዳግም ፡ ከእስራኤል ፡ የተመረጡትን ፡ ሠላሳ ፡ ሺህ ፡ ያህል ፡ ሰው ፡ ሰበሰበ ። ፪ ዳዊትና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ በይሁዳ ፡ ካለች ፡ ከበአል ፡ ተነሥተው ፡ በኪሩቤል ፡ ላይ ፡ በተቀመጠ ፡ በሠራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የተጠራውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ከዚያ ፡ ያመጡ ፡ ፫ ዘንድ ፡ ሄዱ ። የእግዚአብሔርንም ፡ ታቦት ፡ በአዲስ ፡ ሰረገላ ፡ ላይ ፡ ጫኑ ÷ በኮረብታውም ፡ ላይ ፡ ከነበረው ፡ ከአሚናዳብ ፡ ቤት ፡ አመጡት ፤ የአሚናዳብ ፡ ልጆችም ፡ ዖዛ ፡ እና ፡ አሒዮ ፡ ፬ አዲሱን ፡ ሰረገላ ፡ ይነዱ ፡ ነበር ። በኮረብታውም ፡ ላይ ፡ ከነበረው ፡ ከአሚናዳብ ፡ ቤት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ባመጡ ፡ ጊዜ ፡ ፭ አሒዮ ፡ በታቦቱ ፡ ፊት ፡ ይሄድ ፡ ነበር ። ዳዊትና ፡ የእስራኤልም ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ በቅኔና ፡ በበገና ፡ በመሰንቆም ፡ በከበሮም ፡ በነጋሪትና ፡ በጸናጽል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በሙሉ ፡ ኃይላቸው ፡ ይጫወቱ ፡ ነበር ።

፮ ወደ ፡ ናኮንም ፡ አውድማ ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ በሬዎቹ ፡ ይፋንኑ ፡ ነበርና ፡ ዖዛ ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡ ፯ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ያዘ ። የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ በዖዛ ፡ ላይ ፡ ነደደ ÷ እግዚአብሔርም ፡ ስለ ፡ ድፍረቱ ፡ በዚያው ፡ ቀሠፈው ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ታቦት ፡ አጠገብ ፡ በዚያው ፡ ፰ ሞተ ። እግዚአብሔርም ፡ ዖዛን ፡ ስለ ፡ ሰበረው ፡ ዳዊት ፡ አዘነ ፤ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ የዚያ ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ የዖዛ ፡ ስብራት ፡ ተብሎ ፡ ተጠራ ። ፱ በዚያም ፡ ቀን ፡ ዳዊት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈራና ፡— የእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዴት ፡ ይመጣል ? አለ ። ፲ ዳዊትም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ከተማ ፡ ያመጣው ፡ ዘንድ ፡ አልወደደም ፤ ዳዊትም ፡ በጌት ፡ ሰው ፡ በአቢዳራ ፡ ቤት ፡ አገባው ። ፲፩ የእግዚአብሔርም ፡ ታቦት ፡ በጌት ፡ ሰው ፡ በአቢዳራ ፡ ቤት ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ ያህል ፡ ተቀመጠ ፤ እግዚአብሔርም ፡ አቢዳራንና ፡ ቤቱን ፡ ሁሉ ፡ ባረከ ።

፲፪ ንጉሡ ፡ ዳዊትም ፡ እግዚአብሔር ፡ የአቢዳራን ፡ ቤትና ፡ የነበረውን ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ እንደ ፡ ባረከ ፡ ሰማ ። ዳዊትም ፡ ሄዶ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ከአቢዳራ ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ከተማ ፡ በደስታ ፡ አመጣው ። ፲፫ የእግዚአብሔርንም ፡ ታቦት ፡ የተሸከሙ ፡ ስድስት ፡ እርምጃ ፡ በሄዱ ፡ ጊዜ ፡ አንድ ፡ በሬና ፡ ፲፬ አንድ ፡ ፍሪዳ ፡ ሠዋ ። ዳዊትም ፡ በሙሉ ፡ ኃይሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይዘፍን ፡ ነበር ፤ ዳዊትም ፡ የበፍታ ፡ ኤፉድ ፡ ለብሶ ፡ ነበር ። ፲፭ ዳዊትና ፡ የእስራኤልም ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ሆ ፡ እያሉ ፡ ቀንደ ፡ መለከትም ፡ እየነፉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ አመጡ ።

፲፮ የእግዚአብሔርም ፡ ታቦት ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ከተማ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ የሳኦል ፡ ልጅ ፡ ሜልኮል ፡ በመስኮት ፡ ሆና ፡ ተመለከተች ÷ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሲዘልልና ፡ ሲዘፍን ፡ አየች ፤ በልብዋም ፡ ናቀችው ። ፲፯ የእግዚአብሔርንም ፡ ታቦት ፡ አገቡ ÷ ዳዊትም ፡ በተከለለት ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ በስፍራው ፡ አኖሩት ፤ ዳዊትም ፡ የሚቃጠልና ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋዕትን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አሳረገ ። ፲፰ ዳዊትም ፡ የሚቃጠልና ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ ማሳረግ ፡ ከፈጸመ ፡ በኋላ ፡ ሕዝቡን ፡ በሠራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ መረቀ ። ፲፱ ለሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ለእስራኤል ፡ ወገን ፡ ለወንዱም ፡ ለሴቱም ፡ ለእያንዳንዱ ፡ አንዳንድ ፡ እንጀራ ፡ አንዳንድም ፡ የሥጋ ፡ ቍራጭ ፡ አንዳንድም ፡ የዘቢብ ፡ ጥፍጥፍ ፡ አከፋፈለ ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ።

፳ ዳዊትም ፡ ቤተ ፡ ሰቡን ፡ ሊመርቅ ፡ ተመለሰ ። የሳኦልም ፡ ልጅ ፡ ሜልኮል ፡ ዳዊትን ፡ ለመቀበል ፡ ወጣችና ፡— ምናምንቴዎች ፡ እርቃናቸውን ፡ እንደሚገልጡ ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡

በባሪያዎቹ ፡ ቈነጃጅት ፡ ፊት ፡ እርቃኑን ፡ በመ
ግለጡ ፡ ምንኛ ፡ የተከበረ ፡ ነው ፤ አለችው ።
፳፩፤ ዳዊትም ፡ ሚልኮልን ፡— በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ዘፍኛለሁ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡ በእስራ
ኤል ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ ከአባትሽና ፡
ከቤቱ ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ የመረጠኝ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ የተባረከ ፡ ይሁን ፡ ስለዚህም ፡ በእግዚ
፳፪፤ አብሔር ፡ ፊት ፡ እጫወታለሁ ። አሁንም ፡ ከሆ
ንሁት ፡ ይልቅ ፡ የተናቅሁ ፡ እሆናለሁ ፥ በዓይ
ንሽም ፡ እዋረዳለሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በተናገርሽው ፡
፳፫፤ ቈነጃጅት ፡ ዘንድ ፡ እከብራለሁ ፡ አላት ። የሳኦ
ልም ፡ ልጅ ፡ ሚልኮል ፡ እስከ ፡ ሞተችበት ፡
ቀን ፡ ድረስ ፡ ልጅ ፡ አልወለደችም ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ንጉሡ ፡ በቤቱ ፡ በተቀመጠ ፡
ጊዜ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በዙሪያው ፡ ካሉት ፡
፪፤ ጠላቶቹ ፡ ሁሉ ፡ ባሳረፈው ፡ ጊዜ ፥ ንጉሡ ፡
ነቢዩን ፡ ናታንን ፡— እኔ ፡ ከዝግባ ፡ በተሠራ ፡
ቤት ፡ ተቀምጬአለሁ ፥ የእግዚአብሔር ፡
ታቦት ፡ ግን ፡ በመጋረጆች ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡
፫፤ ተቀመጠ ፡ እይ ፡ አለው ። ናታንም ፡ ንጉ
ሡን ፡— እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነውና ፡
ሂድ ፥ በልብህም ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ አድርግ ፡
፬፤ አለው ። በዚያም ፡ ሌሊት ፡ የእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ ወደ ፡ ናታን ፡ መጣ ፡ እንዲህም ፡ አለው ፡—
፭፤፮፤ ሂድ ፥ ለባሪያዬ ፡ ለዳዊት ፡ ንገረው ፡— እግዚአ
ብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የእስራኤልን ፡
ልጆች ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ካወጣሁበት ፡ ቀን ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በድንኳንና ፡ በማ
ደሪያ ፡ እሄድ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በቤት ፡ አልተቀ
መጥሁምና ፡ አንተ ፡ የምኖርበትን ፡ ቤት ፡ አት
፯፤ ሠራልኝም ። ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡
ባለፍሁበት ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡— ስለ ፡ ምን ፡ ቤትን ፡
ከዝግባ ፡ እንጨት ፡ አልሠራችሁልኝም ? ብዬ ፡
ሕዝቤን ፡ እስራኤልን ፡ ይጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ከእ
ስራኤል ፡ ነገድ ፡ ላዘዝሁት ፡ ለአንዱ ፡ በውኑ ፡
፰፤ ተናግሬአለሁን ? አሁንም ፡ ዳዊትን ፡ ባሪያዬን ፡
እንዲህ ፡ በለው ፡— የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— አንተ ፡ መንጋውን ፡
ስትከተል ፡ በሕዝቤ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡
፱፤ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ከበግ ፡ ጥበቃ ፡ ወሰድሁህ ፤ በሄ
ድህበትም ፡ ሁሉ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነበርሁ ፥
ጠላቶችህንም ፡ ሁሉ ፡ ከፊትህ ፡ አጠፋሁ ፤ በም
ድርም ፡ ላይ ፡ እንዳሉ ፡ እንደ ፡ ታላላቆቹ ፡ ስም ፡
፲፤፲፩፤ ታላቅ ፡ ስም ፡ አደርግልሃለሁ ። ለሕዝቤም ፡ ለእ
ስራኤል ፡ ስፍራ ፡ አደርግለታለሁ ፥ እተክለው
ማለሁ ፤ በስፍራውም ፡ ይቀመጣል ፥ ከዚያም ፡
በኋላ ፡ አይናወጥም ፤ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ዘመንና ፡
በሕዝቤ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ፈራጆች ፡ እንዳ
ስነሣሁበት ፡ ጊዜ ፡ ግፈኞች ፡ ተመልሰው ፡ አያ
ስጨንቁትም ፤ ከጠላቶችህም ፡ አሳርፍሃለሁ ።
እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፡— ቤት ፡ እሠራል
፲፪፤ ሃለሁ ፡ ብሎ ፡ ይነግርሃል ። ዕድሜህም ፡ በተፈ
ጸመ ፡ ጊዜ ፡ ከአባቶችህም ፡ ጋር ፡ ባንቀላፋህ ፡
ጊዜ ፥ ከወገብህ ፡ የሚወጣውን ፡ ዘርህን ፡ ከአንተ ፡
በኋላ ፡ አስነሣለሁ ፥ መንግሥቱንም ፡ አጸናለሁ ።
፲፫፤ እርሱ ፡ ለስሜ ፡ ቤት ፡ ይሠራል ፤ የመንግሥቱ
፲፬፤ ንም ፡ ዙፋን ፡ ለዘላለም ፡ አጸናለሁ ። እኔም ፡
አባት ፡ እሆነዋለሁ ፥ እርሱም ፡ ልጅ ፡ ይሆነኛል ፤
ክፉ ፡ ነገርም ፡ ቢያደርግ ፥ ሰው ፡ በሚቀጣበት ፡
በትርና ፡ በሰው ፡ ልጆች ፡ መቅሠፍት ፡ እገሥጸዋ
፲፭፤ ለሁ ፤ ከፊቴም ፡ ከጣልሁት ፡ ከሳኦል ፡ እንዳራ
፲፮፤ ቅሁ ፡ ምሕረቴን ፡ ከእርሱ ፡ አላርቅም ። ቤት
ህና ፡ መንግሥትህም ፡ በፊቴ ፡ ለዘላለም ፡ ይጠ
፲፯፤ ነከራል ፥ ዙፋንህም ፡ ለዘላለም ፡ ይጸናል ። እን
ደዚህ ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ እንደዚህም ፡ ራእይ ፡ ሁሉ ፡
ናታን ፡ ለዳዊት ፡ ነገረው ።

፲፰፤ ንጉሡ ፡ ዳዊትም ፡ ገባ ፥ በእግዚአብሔርም ፡
ፊት ፡ ተቀምጦ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ጌታዬ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ሆይ ፥ እስከዚህ ፡ ያደረስኸኝ ፡ እኔ ፡
፲፱፤ ማን ፡ ነኝ ? ቤቴስ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ጌታዬ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡ በፊትህ ፡ ጥቂት ፡ ነበረ ፤
ስለ ፡ ባሪያህም ፡ ቤት ፡ ደግሞ ፡ ለሩቅ ፡ ዘመን ፡
ተናገርህ ፤ ጌታዬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡
፳፤ የሰው ፡ ሕግ ፡ ነው ። ጌታዬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥
አንተ ፡ ባሪያህን ፡ታውቃለህና ፡ ዳዊትስ ፡ ይናገ
ርህ ፡ ዘንድ ፡ የሚጨምረው ፡ ምንድር ፡ ነው ?
፳፩፤ ለባሪያህም ፡ ታስታውቀው ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ቃልህ ፡
ምክንያትና ፡ እንደ ፡ ልብህ ፡ አሳብ ፡ ይህን ፡ ታላቅ ፡
፳፪፤ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አደረግህ ። ስለዚህም ፥ አቤቱ ፡
አምላኬ ፡ ሆይ ፥ እንደ ፡ አንተ ፡ ያለ ፡ የለምና ፥
በጆሮአችንም ፡ እንደ ፡ ሰማን ፡ ሁሉ ፡ ከአንተ ፡
በቀር ፡ አምላክ ፡ የለምና ፡ አንተ ፡ ታላቅ ፡ ነህ ።
፳፫፤ ለእርሱ ፡ ለራሱ ፡ እንዲሆን ፡ ሕዝብን ፡ ይቤዥ ፡
ዘንድ ፡ ለእርሱ ፡ ለራሱም ፡ ስም ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፥
በአሕዛብና ፡ በአምላኮቻቸውም ፡ ፊት ፡ ከግብጽ ፡
በተቤዠው ፡ ሕዝብ ፡ ፊት ፡ ተአምራትንና ፡
ድንቅን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡
ሄደለት ፡ እንደ ፡ ሕዝብህ ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡
፳፬፤ ያለ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ምን ፡ ሕዝብ ፡ አለ ? ሕዝብ
ህንም ፡ እስራኤልን ፡ ለዘላለም ፡ ሕዝብ ፡ አድ
ርገህ ፡ አጽንተኸዋል ፤ አንተም ፥ አቤቱ ፥ አም
፳፭፤ ላክ ፡ ሆንሃቸዋል ። አቤቱ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ አሁ
ንም ፡ ለባሪያህና ፡ ለቤቱ ፡ የተናገርኸውን ፡ ለዘ
ላለም ፡ አጽናው ፥ እንደ ፡ ተናገርህም ፡ አድርግ ።
፳፮፤ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ የእስራኤል ፡
አምላክ ፡ ነው ፡ ይባል ፡ ዘንድ ፡ ስምህ ፡ ለዘላ
ለም ፡ ታላቅ ፡ ይሁን ፤ የባሪያህም ፡ የዳዊት ፡
፳፯፤ ቤት ፡ በፊትህ ፡ የጸና ፡ ይሁን ። አቤቱ ፡ የእስ
ራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፥
አንተ ፡— እኔ ፡ ቤት ፡ እሠራልሃለሁ ፡ ብለህ ፡
ለባሪያህ ፡ ገልጠሃልና ፡ ስለዚህ ፡ ባሪያህ ፡ ይህ
ችን ፡ ጸሎት ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ይጸልይ ፡ ዘንድ ፡
፳፰፤ በልቡ ፡ ደፈረ ። ጌታዬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥
አሁንም ፡ አንተ ፡ አምላክ ፡ ነህ ፥ ቃልህም ፡
እውነት ፡ ነው ፥ ይህንም ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ለባ
፳፱፤ ሪያህ ፡ ተናግረሃል ። ጌታዬ ፡ እግዚአብሔር ፡

ሆይ ÷ አንተ ፡ ተናግረሃልና ፡ አሁን ፡ እንግዲህ ፡
ለዘላለም ፡ በፊትህ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ የባሪያህን ፡
ቤት ÷ እባክህ ÷ ባርክ ፤ በበረከትህም ፡ የባሪ
ያህ ፡ ቤት ፡ ለዘላለም ፡ ይባረክ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ዳዊት ፡ ፍልስጥኤማውያ
ንን ፡ መታ ÷ አዋረዳቸውም ፤ ከፍልስጥኤማው
ያንም ፡ እጅ ፡ ሜቴግ ፡ አማ ፡ የተባለችውን ፡
ከተማ ፡ ወሰደ ።

፪ ሞዓብን ፡ መታ ÷ ሞዓባውያንንም ፡ በምድር ፡
ጥሎ ፡ በገመድ ፡ ሰፈራቸው ፤ በሁለትም ፡ ገመድ ፡
ለሞት ÷ በአንድም ፡ ገመድ ፡ ሙሉ ፡ ለሕይወት ፡
ሰፈራቸው ፤ ሞዓባውያንም ፡ ለዳዊት ፡ ገባሮች ፡
ሆኑ ÷ ግብርም ፡ አመጡለት ።

፫ ዳዊትም ፡ ደግሞ ፡ በኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ አጠ
ገብ ፡ የነበረውን ፡ ግዛት ፡ መልሶ ፡ ለመያዝ ፡
በሄደ ፡ ጊዜ ፡ የረአብን ፡ ልጅ ፡ የሱባን ፡ ንጉሥ ፡
፬ አድርአዛርን ፡ መታ ። ዳዊትም ፡ ከእርሱ ፡ ሺህ ፡
ሰባት ፡ መቶ ፡ ፈረሰኞች ÷ ሀያ ፡ ሺህም ፡ እግ
ረኞች ፡ ያዘ ፤ ዳዊትም ፡ የሰረገለኛውን ፡ ፈረስ ፡
ሁሉ ፡ ቋንጃ ፡ ቈረጠ ፤ ለመቶ ፡ ሰረገላ ፡ ብቻ ፡
፭ አስቀረ ። ከደማስቆም ፡ ሶርያውያን ፡ የሱባን ፡
ንጉሥ ፡ አድርአዛርን ፡ ሊረዱ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡
ዳዊት ፡ ከሶርያውያን ፡ ሀያ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡
፮ ገደለ ። ዳዊትም ፡ በደማስቆ ፡ ሶርያ ፡ ጭፍሮች ፡
አኖረ ÷ ሶርያውያንም ፡ ለዳዊት ፡ ገባሮች ፡ ሆኑ ÷
ግብርም ፡ አመጡለት ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዳዊት ፡
፯ በሄደበት ፡ ሁሉ ፡ ድልን ፡ ሰጠው ። ዳዊትም ፡
ለአድርአዛር ፡ ባሪያዎች ፡ የነበሩትን ፡ የወርቅ ፡
ጋሾች ፡ ወሰደ ÷ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ይዞአ
፰ ቸው ፡ መጣ ። ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ከአድርአዛር ፡
ከተሞች ፡ ከቤጣሕና ፡ ከቤሮታይ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡
ናስ ፡ ወሰደ ።

፱ የሐማትም ፡ ንጉሥ ፡ ቶዑ ፡ ዳዊት ፡ የአድር
አዛርን ፡ ጭፍራ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ መታ ፡ ሰማ ።
፲ ቶዑም ፡ ከአድርአዛር ፡ ጋር ፡ ሁልጊዜ ፡ ይዋጋ ፡
ነበርና ፡ ዳዊት ፡ አድርአዛርን ፡ ድል ፡ ስለ ፡ መታ ፡
ቶዑ ፡ ልጁን ፡ አዶራምን ፡ ደኅንነቱን ፡ ይጠ
ይቅ ፡ ዘንድ ÷ ይመርቀውም ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡
ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ላከው ፤ እርሱም ፡ የብርና ፡ የወ
፲፩፡፲፪ ርቅ ፡ የናስም ፡ ዕቃ ፡ ይዞ ፡ መጣ ። ንጉሥ ፡
ዳዊትም ፡ ከሸነፋቸው ፡ ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ከሶ
ርያ ፡ ከሞዓብም ፡ ከአሞንም ፡ ልጆች ፡ ከፍልስ
ጥኤማውያንም ፡ ከአማሌቅም ፡ ከረአብም ፡
ልጅ ፡ ከሱባ ፡ ንጉሥ ፡ ከአድርአዛር ፡ ምርኮ ፡
ከቀደሰው ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ ጋር ፡ እነዚህን ፡
ደግሞ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቀደሰ ።

፲፫ ዳዊትም ፡ በተመለሰ ፡ ጊዜ ፡ ከኤዶምያስ ፡
አሥራ ፡ ስምንት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ በጨው ፡
ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ በመምታቱ ፡ ስሙ ፡ ተጠራ ።
፲፬ በኤዶምያስ ፡ ሁሉ ፡ ጭፍሮች ፡ አኖረ ÷ ኤዶማ
ውያንም ፡ ሁሉ ፡ ለዳዊት ፡ ገባሮች ፡ ሆኑ ፤ እግዚ
አብሔርም ፡ ዳዊት ፡ በሚሄድበት ፡ ሁሉ ፡ ድልን ፡
ሰጠው ።

፲፭ ዳዊትም ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነገሠ ፤
ዳዊትም ፡ ለሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ፍርድንና ፡ ጽድቅን ፡
፲፮ አደረገላቸው ። የጽሩያ ፡ ልጅ ፡ ኢዮአብም ፡
የሠራዊት ፡ አለቃ ፡ ነበረ ፤ የአሒሉድም ፡
፲፯ ልጅ ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ ታሪክ ፡ ጸሐፊ ፡ ነበረ ፤ የአኪ
ጦብም ፡ ልጅ ፡ ሳዶቅ ÷ የአቢሜሌክም ፡ ልጅ ፡
አብያታር ፡ ካህናት ፡ ነበሩ ፤ ሠራያም ፡ ጸሐፊ ፡
፲፰ ነበረ ፤ የዮዳሄ ፡ ልጅ ፡ በናያስ ፡ በከሊታውያ
ንና ፡ በፈሊታውያን ፡ ላይ ፡ ነበረ ፤ የዳዊትም ፡
ልጆች ፡ አማካሪዎች ፡ ነበሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ዳዊትም ፦ ስለ ፡ ዮናታን ፡ ቸርነት ፡ አደር
ግለት ፡ ዘንድ ፡ ከሳኦል ፡ ቤት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡
፪ ቀርቶአልን ? አለ ። ከሳኦልም ፡ ቤት ፡ ሲባ ፡
የሚባል ፡ አንድ ፡ ባሪያ ፡ ነበረ ÷ ወደ ፡ ዳዊትም ፡
ጠሩት ፤ ንጉሡም ፦ አንተ ፡ ሲባ ፡ ነህን ?
አለው ። እርሱም ፦ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ነኝ ፡ አለ ።
፫ ንጉሡም ፦ የእግዚአብሔርን ፡ ቸርነት ፡ አደ
ርግለት ፡ ዘንድ ፡ ከሳኦል ፡ ቤት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡
አልቀረምን ? አለ ። ሲባም ፡ ንጉሡን ፦ እግሩ ፡
ሽባ ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ የዮናታን ፡ ልጅ ፡ አለ ፡
፬ አለው ። ንጉሡም ፦ ወዴት ፡ ነው ? አለው ፤
ሲባም ፡ ንጉሡን ፦ እነሆ ÷ እርሱ ፡ በሎዶባር ፡
በዓሚኤል ፡ ልጅ ፡ በማኪር ፡ ቤት ፡ አለ ፡ አለው ።
፭ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ልኮ ፡ ከሎዶባር ፡ ከዓሚኤል ፡
፮ ልጅ ፡ ከማኪር ፡ ቤት ፡ አስመጣው ። የሳኦልም ፡
ልጅ ፡ የዮናታን ፡ ልጅ ፡ ሜምፌቦስቴ ፡ ወደ ፡
ዳዊት ፡ መጣ ÷ በግምባሩም ፡ ወድቆ ፡ እጅ ፡
ነሣ ፤ ዳዊትም ፦ ሜምፌቦስቴ ፡ ሆይ ÷ አለ ፤
፯ እርሱም ፦ እነሆኝ ፡ ባሪያህ ፡ አለ ። ዳዊትም ፦
ስለ ፡ አባትህ ፡ ስለ ፡ ዮናታን ፡ ቸርነት ፡ ፈጽሜ ፡
አደርግልሃለሁና ፡ አትፍራ ፤ የአባትህንም ፡
የሳኦልን ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ እመልስልሃለሁ ÷
አንተም ፡ ሁልጊዜ ፡ ከገበታዬ ፡ እንጀራ ፡ ትበ
፰ ላለህ ፡ አለው ። እርሱም ፦ የሞተ ፡ ውሻ ፡
ወደምመስል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ የተመለከትህ ፡ እኔ ፡
ባሪያህ ፡ ምንድር ፡ ነኝ ? ብሎ ፡ እጅ ፡ ነሣ ።

፱ ንጉሡም ፡ የሳኦልን ፡ ባሪያ ፡ ሲባን ፡ ጠርቶ ፦
ለሳኦልና ፡ ለቤቱ ፡ ሁሉ ፡ የነበረውን ፡ ሁሉ ፡
፲ ለጌታህ ፡ ልጅ ፡ ሰጥቻለሁ ። አንተና ፡ ልጆችህ ፡
ሎሌዎችህም ፡ ምድሩን ፡ እረሱለት ፤ ለጌታህም ፡
ልጅ ፡ እንጀራ ፡ ይሆነው ፡ ዘንድ ፡ ፍሬውን ፡
አግባ ፤ የጌታህ ፡ ልጅ ፡ ሜምፌቦስቴ ፡ ግን ፡
ሁልጊዜ ፡ ከገበታዬ ፡ ይበላል ፡ አለው ። ለሲ
ባም ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡ ልጆችና ፡ ሀያ ፡ ባሪያ
፲፩ ዎች ፡ ነበሩት ። ሲባም ፡ ንጉሡን ፦ ጌታዬ ፡
ንጉሡ ፡ ባሪያውን ፡ እንዳዘዘ ፡ እንዲሁ ፡ ባሪያህ ፡
ያደርጋል ፡ አለው ። ሜምፌቦስቴም ፡ ከንጉሡ ፡
ልጆች ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ከዳዊት ፡ ገበታ ፡ ይበላ ፡
፲፪ ነበር ። ለሜምፌቦስቴም ፡ ሚካ ፡ የተባለ ፡
ታናሽ ፡ ልጅ ፡ ነበረው ። በሲባም ፡ ቤት ፡ ያሉ ፡
፲፫ ሁሉ ፡ ለሜምፌቦስቴ ፡ ያገለግሉ ፡ ነበር ። ሜም

ፌቦስቴም፡ከንጉሥ፡ገበታ፡ሁልጊዜ፡እየበላ፡
በኢየሩሳሌም፡ተቀምጦ፡ነበር፤ ሁለት፡እግ
ሩም፡ሽባ፡ነበረ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፤ ከዚህ፡በኋላ፡የአሞን፡ልጆች፡ንጉሥ፡
ሞተ ፥ ልጁም፡ሐኖን፡በፋንታው፡ነገሠ።
፪፤ ዳዊትም ፡— አባቱ፡ወረታ፡እንዳደረገልኝ፡
እኔ፡ለናዖስ፡ልጅ፡ለሐኖን፡ቸርነት፡አደር
ጋለሁ፡አለ። ዳዊትም፡አባቱ፡ስለ፡ሞተ፡
ሊያጽናናው፡ባሪያዎቹን፡ላከ፤ የዳዊትም፡
ባሪያዎች፡ወደ፡አሞን፡ልጆች፡አገር፡መጡ።
፫፤ የአሞንም፡ልጆች፡አለቆች፡ጌታቸውን፡
ሐኖንን ፡— ዳዊት፡አባትህን፡አክብሮ፡ሊያ
ጽናናህ፡ባሪያዎቹን፡ወደ፡አንተ፡የላከ፡ይመ
ስልሃልን? ዳዊትስ፡ከተማይቱን፡ለመመርመ
ርና፡ለመሰለል፡ለማጥፋትም፡ባሪያዎቹን፡
፬፤ የላከ፡አይደለምን? አሉት። ሐኖንም፡የዳ
ዊትን፡ባሪያዎች፡ወስዶ፡የጢማቸውን፡ገሚስ፡
ላጨ ፥ ልብሳቸውንም፡እስከ፡ወገባቸው፡
፭፤ ድረስ፡ከሁለት፡ቀድዶ፡ሰደዳቸው። ዳዊ
ትም፡ያን፡በሰማ፡ጊዜ፡ሰዎቹ፡እጅግ፡አፍ
ረው፡ነበሩና፡ተቀባዮች፡ላከ። ንጉሡም ፡—
ጢማችሁ፡እስኪያድግ፡ድረስ፡በኢያሪኮ፡
ተቀመጡ ፥ ከዚያም፡በኋላ፡ተመለሱ፡አላ
ቸው።

፮፤ የአሞን፡ልጆች፡በዳዊት፡ዘንድ፡እንደ፡
ተጠሉ፡ባዩ፡ጊዜ ፥ የአሞን፡ልጆች፡ልከው፡
ከሶርያውያን፡ከቤትሮዖብና፡ከሱባ፡ሀያ፡
ሺህ፡እግረኞች ፥ ከመዓካ፡ንጉሥም፡አንድ፡
ሺህ፡ሰዎች ፥ ከጦብም፡አሥራ፡ሁለት፡ሺህ፡
፯፤ ሰዎች፡ቀጠሩ። ዳዊትም፡በሰማ፡ጊዜ፡ኢዮ
አብንና፡የኃያላኑን፡ሠራዊት፡ሁሉ፡ላከ።
፰፤ የአሞንም፡ልጆች፡ወጥተው፡በበሩ፡መግ
ቢያ፡ፊት፡ለፊት፡ተሰለፉ፤ የሱባና፡የረአብ፡
ሶርያውያን ፥ የጦብና፡የመዓካም፡ሰዎች፡ለብ
ቻቸው፡በሰፊ፡ሜዳ፡ላይ፡ነበሩ።
፱፤ ኢዮአብም፡በፊትና፡በኋላ፡ሰልፍ፡እንደ፡
ከበበው፡በየ፡ጊዜ፡ከእስራኤል፡ምርጥ፡ምር
ጦቹን፡ሁሉ፡መረጠ ፥ በሶርያውያንም፡ፊት፡
፲፤ ለሰልፍ፡አኖራቸው። የቀረውንም፡ሕዝብ፡
በወንድሙ፡በአቢሳ፡እጅ፡አድርጎ፡በአ
ሞን፡ልጆች፡ፊት፡ለሰልፍ፡አኖራቸው።
፲፩፤ ሶርያውያን፡ቢበረቱብኝ፡ትረዳኛለህ፤ የአ
ሞን፡ልጆች፡ቢበረቱብህ፡እኔ፡መጥቼ፡እረ
፲፪፤ ዳሃለሁ። አይዞህ፤ ስለ፡ሕዝባችንና፡ስለ፡
አምላካችንም፡ከተሞች፡እንበርታ፤ እግዚአ
ብሔርም፡ደስ፡ያሰኘውን፡ያድርግ፡አለ።
፲፫፤ ኢዮአብና፡ከእርሱም፡ጋር፡የነበረው፡ሕዝብ፡
ከሶርያውያን፡ጋር፡ሊዋጉ፡ቀረቡ ፥ እነር
፲፬፤ ሱም፡ከፊቱ፡ሸሹ። የአሞንም፡ልጆች፡
ሶርያውያን፡እንደ፡ሸሹ፡ባዩ፡ጊዜ፡እነርሱ፡
ደግሞ፡ከአቢሳ፡ፊት፡ሸሹ ፥ ወደ፡ከተማይ
ቱም፡ገቡ፤ ኢዮአብም፡ከአሞን፡ልጆች፡
ዘንድ፡ተመልሶ፡ወደ፡ኢየሩሳሌም፡መጣ።
፲፭፤ ሶርያውያንም፡በእስራኤል፡ፊት፡እንደ፡
ተሸነፉ፡ባዩ፡ጊዜ፡በአንድነት፡ተሰበሰቡ።
፲፮፤ አድርአዛርም፡ልኮ፡በወንዝ፡ማዶ፡የነበሩትን፡
ሶርያውያን፡አመጣ፤ ወደ፡ኤላምም፡መጡ ፥
የአድርአዛርም፡ሠራዊት፡አለቃ፡ሶባክ፡በፊ
፲፯፤ ታቸው፡ነበረ። ዳዊትም፡በሰማ፡ጊዜ፡እስራ
ኤልን፡ሁሉ፡ሰበሰበ ፥ ዮርዳኖስንም፡ተሻግሮ፡
ወደ፡ኤላም፡መጣ፤ ሶርያውያንም፡በዳዊት፡
ፊት፡ተሰልፈው፡ከእርሱ፡ጋር፡ተዋጉ።
፲፰፤ ሶርያውያንም፡ከእስራኤል፡ፊት፡ሸሹ፤ ዳዊ
ትም፡ከሶርያውያን፡ሰባት፡መቶ፡ሰረገለኞች፡
አርባ፡ሺህም፡ፈረሰኞች፡ገደለ፤ የሠራዊቱ
ንም፡አለቃ፡ሶባክን፡መታ ፥ እርሱም፡በዚያ፡
፲፱፤ ሞተ። ለአድርአዛርም፡የሚገብሩ፡ነገሥታት፡
ሁሉ፡በእስራኤል፡ፊት፡እንደ፡ተሸነፉ፡ባዩ፡
ጊዜ፡ከእስራኤል፡ጋር፡ታረቁ ፥ ገበሩላቸውም።
ሶርያውያንም፡ከዚያ፡ወዲያ፡የአሞንን፡ልጆች፡
ይረዱ፡ዘንድ፡ፈሩ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩፤ እንዲህም፡ሆነ፤ በዓመቱ፡መለወጫ፡ነገ
ሥታት፡ወደ፡ሰልፍ፡በሚወጡበት፡ጊዜ ፥
ዳዊት፡ኢዮአብን፡ከእርሱም፡ጋር፡ባሪያዎ
ቹን፡እስራኤልንም፡ሁሉ፡ሰደደ። የአሞን
ንም፡ልጆች፡አገር፡አጠፉ ፥ ረባትንም፡ከበቡ፤
ዳዊት፡ግን፡በኢየሩሳሌም፡ቀርቶ፡ነበር።
፪፤ እንዲህም፡ሆነ፤ ወደ፡ማታ፡ጊዜ፡ዳዊት፡
ከምንጣፉ፡ተነሣ ፥ በንጉሥም፡ቤት፡በሰገነት፡
ላይ፡ተመላለሰ፤ በሰገነቱ፡ሳለ፡አንዲት፡ሴት፡
ስትታጠብ፡አየ፤ ሴቲቱም፡መልከ፡መልካም፡
፫፤ ነበረች። ዳዊትም፡ልኮ፡ስለ፡ሴቲቱ፡ጠየቀ፤
አንድ፡ሰውም ፡— ይህች፡የኤልያብ፡ልጅ፡
የኬጢያዊው፡የኦርዮ፡ሚስት፡ቤርሳቤህ፡አይ
፬፤ ደለችምን? አለ። ዳዊትም፡መልእክተኞች፡
ልኮ፡አስመጣት፤ ወደ፡እርሱም፡ገባች ፥ ከር
ኩሰትዋም፡ነጽታ፡ነበርና፡ከእርስዋ፡ጋር፡
፭፤ ተኛ፤ ወደ፡ቤትዋም፡ተመለሰች። ሴቲቱም፡
አረገዘች ፥ ወደ፡ዳዊትም ፡— አርግዤአለሁ፡
ብላ፡ላከችበት።
፮፤ ዳዊትም፡ወደ፡ኢዮአብ ፡— ኬጢያዊውን፡
ኦርዮን፡ስደድልኝ፡ብሎ፡ላከ። ኢዮአብም፡
፯፤ ኦርዮን፡ወደ፡ዳዊት፡ሰደደው። ኦርዮም፡
ወደ፡እርሱ፡በመጣ፡ጊዜ፡ዳዊት፡የኢዮአ
ብንና፡የሕዝቡን፡ደኅንነት ፥ ሰልፉም፡እን
፰፤ ዴት፡እንደ፡ሆነ፡ጠየቀው። ዳዊትም፡ኦር
ዮን፡— ወደ፡ቤትህ፡ሂድ ፥ እግርህንም፡ታጠብ፡
አለው። ኦርዮም፡ከንጉሡ፡ቤት፡ሲወጣ፡ማለ
ፊያ፡የንጉሥ፡መብል፡ተከተሎት፡ሄደ።
፱፤ ኦርዮ፡ግን፡ከጌታው፡ባሪያዎች፡ሁሉ፡ጋር፡
በንጉሥ፡ቤት፡ደጅ፡ተኛ ፥ ወደ፡ቤቱም፡
፲፤ አልወረደም። ኦርዮ፡ወደ፡ቤቱ፡አልሄደም፡
ብለው፡ለዳዊት፡ነገሩት፤ ዳዊትም፡ኦርዮን ፡—
አንተ፡ከመንገድ፡የመጣህ፡አይደለምን? ስለ፡

ምን ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ አልወረድህም ? አለው ።
፲፩ ኦርዮም ፡ ዳዊትን ፡— ታቦቱና ፡ እስራኤል ፡ ይሁ
ዳም ፡ በጎጆ ፡ ተቀምጠዋል ፤ ጌታዬ ፡ ኢዮአ
ብና ፡ የጌታዬም ፡ ባሪያዎች ፡ በሰፊ ፡ ሜዳ ፡ ሰፍረ
ዋል ፤ እኔ ፡ ልበላና ፡ ልጠጣ ፡ ወይስ ፡ ከሚስቴ ፡
ጋር ፡ ልተኛ ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ እሄዳለሁን ? በሕይ
ወትህና ፡ በሕያው ፡ ነፍስህ ፡ እምላለሁ ! ይህን ፡
፲፪ ነገር ፡ አላደርገውም ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ ኦር
ዮን ፡— ዛሬ ፡ ደግሞ ፡ በዚህ ፡ ተቀመጥ ÷ ነገም ፡
አሰናብትሃለሁ ፡ አለው ። ኦርዮም ፡ በዚያ ፡
ቀንና ፡ በነጋው ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተቀመጠ ።
፲፫ ዳዊትም ፡ ጠራው ÷ በፊቱም ፡ በላና ፡ ጠጣ ÷
አሰከረውም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡ ወጥቶ ፡
ከጌታው ፡ ባሪያዎች ፡ ጋር ፡ በምንጣፉ ፡ ላይ ፡
ተኛ ÷ ወደ ፡ ቤቱም ፡ አልወረደም ።

፲፬ በነጋም ፡ ጊዜ ፡ ዳዊት ፡ ለኢዮአብ ፡ ደብዳቤ ፡
፲፭ ጻፈ ÷ በኦርዮም ፡ እጅ ፡ ላከው ። በደብዳቤ
ውም ፡— ኦርዮን ፡ ጽኑ ፡ ሰልፍ ፡ ባለበት ፡ በፊ
ተኛው ፡ ስፍራ ፡ አቁሙት ÷ ተመትቶም ፡
ይሞት ፡ ዘንድ ፡ ከኋላው ፡ ሽሹ ፡ ብሎ ፡ ጻፈ ።
፲፮ ኢዮአብም ፡ ከተማይቱን ፡ በከበበ ፡ ጊዜ ፡ ጀግ
ኖች ፡ እንዳሉበት ፡ በሚያውቀው ፡ ስፍራ ፡ ኦር
፲፯ ዮን ፡ አቆመው ። የከተማይቱም ፡ ሰዎች ፡ ወጥ
ተው ፡ ከኢዮአብ ፡ ጋር ፡ ተዋጉ ፤ ከዳዊትም ፡
ባሪያዎች ፡ ከሕዝቡ ፡ አንዳንዱ ፡ ወደቁ ፤ ኬጢ
፲፰ ያዊው ፡ ኦርዮም ፡ ደግሞ ፡ ሞተ ። ኢዮአብም ፡
ልከ ፡ በሰልፍ ፡ የሆነውን ፡ ሁሉ ፡ ለዳዊት ፡ ነገ
፲፱ ረው ። ለመልእክተኛውም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘ
ዘው ፡— የሰልፉን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ለንጉሡ ፡ ነግ
፳ ረህ ፡ በፈጸምህ ፡ ጊዜ ፡— ስትዋጉ ፡ ወደ ፡ ከተ
ማይቱ ፡ ለምን ፡ ቀረባችሁ ? ከቅጥሩ ፡ በላይ ፡
፳፩ ፍላጻ ፡ እንዲወረወር ፡ አታውቁምን ? የሩቤ
ሼትን ፡ ልጅ ፡ አቤሜሌክን ፡ ማን ፡ ገደለው ?
ከቅጥር ፡ ላይ ፡ የወፍጮ ፡ መጅ ፡ ጥላ ፡ በቴቤስ ፡
ላይ ፡ የገደለችው ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ አይደለች
ምን ? ስለ ፡ ምን ፡ ወደ ፡ ቅጥሩ ፡ እንደዚህ ፡
ቀረባችሁ ? ብሎ ፡ ንጉሡ ፡ ሲቈጣ ፡ ብታይ ÷
አንተ ፡— ባሪያህ ፡ ኬጢያዊው ፡ ኦርዮ ፡ ደግሞ ፡
ሞተ ፡ በለው ።

፳፪ መልእክተኛውም ፡ ተነሥቶ ፡ ሄደ ÷ ኢዮአ
፳፫ ብም ፡ ያዘዘውን ፡ ሁሉ ፡ ለዳዊት ፡ ነገረው ። መል
እክተኛውም ፡ ዳዊትን ፡— ሰዎቹ ፡ በረቱብን ÷
ወደ ፡ ሜዳም ፡ ወጡብን ፤ እኛም ፡ ወደቅንባ
ቸው ÷ እስከ ፡ ከተማይቱም ፡ በር ፡ ድረስ ፡ ተከ
፳፬ ተልናቸው ። ፍላጻ ፡ የሚወረውሩም ፡ በቅጥሩ ፡
ላይ ፡ ሆነው ፡ በባሪያዎችህ ፡ ላይ ፡ ወረወሩ ፤ ከንጉ
ሡም ፡ ባሪያዎች ፡ አንዳንድ ፡ ሞቱ ÷ ባሪያህም ፡
ኬጢያዊው ፡ ኦርዮ ፡ ደግሞ ፡ ሞተ ፡ አለው ።
፳፭ ዳዊትም ፡ መልእክተኛውን ፡— ሰይፍ ፡ አንድ ፡
ጊዜ ፡ ይህን ፡ አንድ ፡ ጊዜም ፡ ያን ፡ ያጠፋልና ፡
ይህ ፡ ነገር ፡ በዓይንህ ፡ አይከፋ ፤ ከተማይቱን ፡
የሚወጉትን ፡ አበርታ ÷ አፍርሳትም ፡ ብለህ ፡
ለኢዮአብ ፡ ንገረው ፤ አንተም ፡ አጽናው ፡
አለው ።

የኦርዮም ፡ ሚስት ፡ ባልዋ ፡ ኦርዮ ፡ እንደ ፡ ፳፮
ሞተ ፡ በሰማች ፡ ጊዜ ፡ ለባልዋ ፡ አለቀሰች ።
የልቅሶዋም ፡ ወራት ፡ ሲፈጸም ፡ ዳዊት ፡ ልኮ ፡ ፳፯
ወደ ፡ ቤቱ ፡ አስመጣት ÷ ሚስትም ፡ ሆነችው ÷
ወንድ ፡ ልጅም ፡ ወለደችለት ፤ ነገር ፡ ግን ፡
ዳዊት ፡ ያደረገው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ሆነ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

እግዚአብሔርም ፡ ናታንን ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ላከ ÷ ፩
ወደ ፡ እርሱም ፡ መጥቶ ፡ አለው ፡— በአንድ ፡
ከተማ ፡ አንዱ ፡ ባለጠጋ ፡ አንዱም ፡ ድሀ ፡ የሆኑ ፡
ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ። ባለጠጋውም ፡ እጅግ ፡ ፪
ብዙ ፡ በግና ፡ ላም ፡ ነበረው ። ለድሀው ፡ ግን ፡ ፫
ከገዛት ፡ አንዲት ፡ ታናሽ ፡ በግ ፡ በቀር ፡ አንዳች ፡
አልነበረውም ፤ አሳደጋትም ÷ ከልጆቹም ፡ ጋር ፡
በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ አደገች ፤ እንጀራውንም ፡
ትበላ ÷ ከዋንጫውም ፡ ትጠጣ ÷ በብብቱም ፡
ትተኛ ፡ ነበር ÷ እንደ ፡ ልጁም ፡ ነበረች ። ወደ ፡ ፬
ባለጠጋውም ፡ እንግዳ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ከበጉና ፡
ከላሙ ፡ ወስዶ ፡ ለዚያ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ለመጣው ፡
እንግዳ ፡ ያዘጋጅለት ፡ ዘንድ ፡ ሳሳ ፤ የዚያንም ፡
የድሀውን ፡ ሰው ፡ በግ ፡ ወስዶ ፡ ለዚያ ፡ ለመ
ጣው ፡ ሰው ፡ አዘጋጀ ። ዳዊትም ፡ በዚያ ፡ ሰው ፡ ፭
ላይ ፡ እጅግ ፡ ተቈጥቶ ፡ ናታንን ፡— ሕያው ፡
እግዚአብሔርን ! ይህን ፡ ያደረገ ፡ ሰው ፡ የሞት ፡
ልጅ ፡ ነው ። ይህን ፡ አድርጎአልና ÷ አላዘነምና ፡ ፮
ስለ ፡ አንዲቱ ፡ በግ ፡ አራት ፡ ይመልስ ፡ አለው ።

ናታንም ፡ ዳዊትን ፡ አለው ፡— ያ ፡ ሰው ፡ ፯
አንተ ፡ ነህ ። የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በእስራኤል ፡ ላይ ፡
ንጉሥ ፡ ልትሆን ፡ ቀባሁህ ÷ ከሳኦልም ፡ እጅ ፡
አዳንሁህ ፤ የጌታህንም ፡ ቤት ፡ ሰጠሁህ ÷ የጌ ፰
ታህንም ፡ ሚስቶች ፡ በብብትህ ፡ ጣልሁልህ ፤
የእስራኤልንና ፡ የይሁዳን ፡ ቤት ፡ ሰጠሁህ ፤
ይህም ፡ አንሶ ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ ከዚህ ፡ የበለጠ ፡
እጨምርልህ ፡ ነበር ። አሁንስ ፡ በፊቱ ፡ ክፉ ፡ ፱
ትሠራ ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ነገር ፡ ለምን ፡
አቃለልህ ? ኬጢያዊውን ፡ ኦርዮን ፡ በሰይፍ ፡
መትተሃል ÷ ሚስቱንም ፡ ለአንተ ፡ ሚስት ፡
ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ወስደሃል ፤ እርሱንም ፡ በአሞን ፡
ልጆች ፡ ሰይፍ ፡ ገድለሃል ። ስለዚህም ፡ አቃልለ ፲
ኸኛልና ÷ የኬጢያዊውንም ፡ የኦርዮን ፡ ሚስት ፡
ለአንተ ፡ ሚስት ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ወስደሃልና ፡
ለዘላለም ፡ ከቤትህ ፡ ሰይፍ ፡ አይርቅም ። እግ ፲፩
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ ከቤትህ ፡
ክፉ ፡ ነገር ፡ አስነሣብሃለሁ ፤ ሚስቶችህንም ፡
በዓይንህ ፡ ፊት ፡ እወስዳለሁ ÷ ለዘመድህም ፡
እሰጣቸዋለሁ ÷ በዚህችም ፡ ፀሐይ ፡ ዓይን ፡
ፊት ፡ ከሚስቶችህ ፡ ጋር ፡ ይተኛል ። አንተ ፡ ፲፪
ይህን ፡ በስውር ፡ አድርገኸዋል ፤ እኔ ፡ ግን ፡
ይህን ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ፊትና ፡ በፀሐይ ፡
ፊት ፡ አደርገዋለሁ ። ዳዊትም ፡ ናታንን ፡— እግ ፲፫
ዚአብሔርን ፡ በድያለሁ ፡ አለው ። ናታንም ፡

ዳዊትን ፡— እግዚአብሔር ፡ ደግሞ ፡ ኃጢአትህን ፡ አርቆልሃል ፤ አትሞትም ። ፲፬ ነገር ፡ ግን ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጠላቶች ፡ ታላቅ ፡ የስድብ ፡ ምክንያት ፡ አድርገሃልና ፡ ስለዚህ ፡ ደግሞ ፡ የተወለደልህ ፡ ልጅ ፡ ፈጽሞ ፡ ይሞታል ፡ አለው ። ፲፭ ናታንም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመለሰ ።

እግዚአብሔርም ፡ የኦርዮ ፡ ሚስት ፡ ለዳዊት ፡ የወለደችውን ፡ ሕፃን ፡ ቀሠፈ ፥ እጅግም ፡ ታምሞ ፡ ነበር ። ፲፮ ዳዊትም ፡ ስለ ፡ ሕፃኑ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመነ ፤ ዳዊትም ፡ ጾመ ፥ ገብቶም ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ ተኛ ። ፲፯ የቤቱም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ተነሥተው ፡ ከምድር ፡ ያነሡት ፡ ዘንድ ፡ በአጠገቡ ፡ ቆሙ ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ እንቢ ፡ አለ ፥ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ እንጀራ ፡ አልበላም ። ፲፰ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ ሕፃኑ ፡ ሞተ ። የዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡— ሕፃኑ ፡ በሕይወት ፡ ሳለ ፡ ብንነግረው ፡ አልሰማንም ፤ ይልቁንስ ፡ ሕፃኑ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ብንነግረው ፡ እንዴት ፡ ይሆን ? በነፍሱ ፡ ክፉ ፡ ያደርጋል ፡ ብለው ፡ ሕፃኑ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ይነግሩት ፡ ዘንድ ፡ ፈሩ ። ፲፱ ዳዊትም ፡ ባሪያዎቹ ፡ በሹክሹክታ ፡ ሲነጋገሩ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ዳዊት ፡ ሕፃኑ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ አወቀ ፤ ዳዊትም ፡ ባሪያዎቹን ፡— ሕፃኑ ፡ ሞቶአል ? አላቸው ። እነርሱም ፡— ሞቶአል ፡ አሉት ። ፳ ዳዊትም ፡ ከምድር ፡ ተነሥቶ ፡ ታጠበ ፥ ተቀባም ፥ ልብሱንም ፡ ለወጠ ፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ገብቶ ፡ ሰገደ ። ወደ ፡ ቤቱም ፡ መጣ ፡— እንጀራ ፡ አምጡልኝ ፡ አለ ፤ በፊቱም ፡ አቀረቡለት ፥ በላም ። ፳፩ ባሪያዎቹም ፡— ይህ ፡ ያደረግኸው ፡ ነገር ፡ ምንድር ፡ ነው ? በሕይወት ፡ ሳለ ፡ ስለ ፡ ሕፃኑ ፡ ጾምህና ፡ አለቀስህ ፤ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ተነሥተህ ፡ እንጀራ ፡ በላህ ፡ አሉት ። ፳፪ እርሱም ፡— ሕፃኑ ፡ ሕያው ፡ ሳለ ፡— እግዚአብሔር ፡ ይምረኝ ፥ ሕፃኑም ፡ በሕይወት ፡ ይኖር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ማን ፡ ያውቃል ? ብዬ ፡ ጾምሁ ፡ አለቀስሁም ። ፳፫ አሁን ፡ ግን ፡ ሞቶአል ፤ የምጾመው ፡ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ? በውኑ ፡ እንግዲህ ፡ እመልሰው ፡ ዘንድ ፡ ይቻለኛልን ? እኔ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ እሄዳለሁ ፡ እንጂ ፡ እርሱ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አይመለስም ፡ አለ ።

፳፬ ዳዊትም ፡ ሚስቱን ፡ ቤርሳቤህን ፡ አጽናናት ፥ ወደ ፡ እርስዋም ፡ ገባ ፥ ከእርስዋም ፡ ጋር ፡ ተኛ ፤ ወንድ ፡ ልጅም ፡ ወለደች ፥ ስሙንም ፡ ሰሎሞን ፡ ብሎ ፡ ጠራው ። እግዚአብሔርም ፡ ወደደው ፤ ፳፭ ደግሞም ፡ በነቢዩ ፡ በናታን ፡ እጅ ፡ ልኮ ፡ ስሙን ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይዲድያ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።

፳፮ ኢዮአብም ፡ የአሞንን ፡ ልጆች ፡ ከተማ ፡ ረባትን ፡ ወጋ ፥ የውኃውንም ፡ ከተማ ፡ ያዘ ። ፳፯ ኢዮአብም ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡— ረባትን ፡ ወግቻለሁ ፥ የውኃውንም ፡ ከተማ ፡ ይዤአለሁ ። ፳፰ አሁንም ፡ ከተማይቱን ፡ እንዳልይዝ ፥ በስሜም ፡ እንዳትጠራ ፥ የቀረውን ፡ ሕዝብ ፡ ሰብስብ ፥ ከተማይቱንም ፡ ከብበህ ፡ ያዝ ፡ ብሎ ፡ መልእክተኞችን ፡ ላከ ። ፳፱ ዳዊትም ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ሰብስቦ ፡ ወደ ፡ ረባት ፡ ሄደ ፥ ወግቶም ፡ ያዛት ። ፴ የንጉሣቸውንም ፡ ዘውድ ፡ ከራሱ ፡ ላይ ፡ ወሰደ ። ክብደቱም ፡ አንድ ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፡ ያህል ፡ ነበር ፥ ከቡር ፡ ዕንቍም ፡ ነበረበት ፤ ዳዊትም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ አደረገው ። ከከተማይቱም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ምርኮ ፡ አወጣ ። ፴፩ በውስጥዋም ፡ የነበሩትን ፡ ሕዝብ ፡ አውጥቶ ፡ በመጋዝና ፡ በብረት ፡ መቈፈሪያና ፡ በብረት ፡ መጥረቢያ ፡ እንዲሠሩ ፡ አደረጋቸው ፤ የሸክላ ፡ ጡብም ፡ እንዲያቃጥሉ ፡ አደረጋቸው ፤ በአሞን ፡ ልጆች ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ አደረገ ። ዳዊትም ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ ለዳዊት ፡ ልጅ ፡ ለአቤሴሎም ፡ አንዲት ፡ የተዋበች ፡ እኅት ፡ ነበረችው ፥ ስምዋም ፡ ትዕማር ፡ ነበረ ፤ የዳዊትም ፡ ልጅ ፡ አምኖን ፡ ወደዳት ። ፪ አምኖንም ፡ ከእኅቱ ፡ ከትዕማር ፡ የተነሣ ፡ እጅግ ፡ ስለ ፡ ተከዘ ፡ ታመመ ፤ ድንግልም ፡ ነበረችና ፡ አንዳች ፡ ያደርጋት ፡ ዘንድ ፡ በዓይኑ ፡ ፊት ፡ ጭንቅ ፡ ሆኖበት ፡ ነበር ። ፫ ለአምኖንም ፡ የዳዊት ፡ ወንድም ፡ የሳምዓ ፡ ልጅ ፡ ኢዮናዳብ ፡ የሚባል ፡ ወዳጅ ፡ ነበረው ፤ ኢዮናዳብም ፡ እጅግ ፡ ብልህ ፡ ሰው ፡ ነበረ ። ፬ እርሱም ፡— የንጉሥ ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ስለ ፡ ምን ፡ ቀን ፡ በቀን ፡ እንዲህ ፡ ከሳህ ? አትነግረኝምን ? አለው ። አምኖንም ፡— የወንድሜን ፡ የአቤሴሎምን ፡ እኅት ፡ ትዕማርን ፡ እወድዳታለሁ ፡ አለው ። ፭ ኢዮናዳብም ፡— ታምሜአለሁ ፡ ብለህ ፡ በአልጋህ ፡ ላይ ፡ ተኛ ፤ አባትህም ፡ ሊያይህ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡— እኅቴ ፡ ትዕማር ፡ እንድትመጣና ፡ እኔ ፡ የምበላውን ፡ እንጀራ ፡ እንድትሰጠኝ ፥ መብሉንም ፡ እኔ ፡ እያየሁ ፡ እንድታዘጋጅልኝ ፥ ከእጅዋም ፡ እንድበላው ፡ እለምንሃለሁ ፡ በል ፡ አለው ። ፮ እንዲሁም ፡ አምኖን ፡— ታምሜአለሁ ፡ ብሎ ፡ ተኛ ፤ ንጉሡም ፡ ሊያየው ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ አምኖን ፡ ንጉሡን ፡— እኅቴ ፡ ትዕማር ፡ እንድትመጣና ፡ እኔ ፡ እያየሁ ፡ ሁለት ፡ እንጎቻ ፡ እንድታደርግልኝ ፥ ከእጅዋም ፡ እንድበላ ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለው ።

፯ ዳዊትም ፡— መብልን ፡ ታዘጋጂለት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ወንድምሽ ፡ ወደ ፡ አምኖን ፡ ቤት ፡ ሂጂ ፡ ብሎ ፡ መልእክተኞችን ፡ ወደ ፡ ትዕማር ፡ ቤት ፡ ላከ ። ፰ ትዕማርም ፡ ወደ ፡ ወንድምዋ ፡ ወደ ፡ አምኖን ፡ ቤት ፡ ሄደች ፥ ተኝቶም ፡ ነበር ፤ ዱቄትም ፡ ወስዳ ፡ ለወሰች ፥ እያየም ፡ እንጎቻ ፡ አደረገች ፥ ጋገረችም ። ፱ ምጣዱንም ፡ ወስዳ ፡ በፊቱ ፡ ገለበጠች ፡ እርሱ ፡ ግን ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ አለ ። አምኖንም ፡— ሰውን ፡ ሁሉ ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ አስወጡ ፡ አለ ፤ ሰውም ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ። ፲ አምኖንም ፡ ትዕማርን ፡— ከእጅሽ ፡ እበላ ፡ ዘንድ ፡ መብሉን ፡ ወደ ፡ እልፍኙ ፡ አግቢው ፡ አላት ፤ ትዕማርም ፡ የሠራችውን ፡ እንጎቻ ፡ ወስዳ ፡ ወንድምዋ ፡

አምኖን ፡ ወዳለበት ፡ እልፍኝ ፡ አገባችው ። ፲፩ መብሉንም ፡ ባቀረበች ፡ ጊዜ ፡ ያዛትና ፡— እኅቴ ፡ ሆይ ÷ ነዪ ፡ ከእኔም ፡ ጋር ፡ ተኚ ፡ አላት ። ፲፪ እርስዋ ፡ መልሳ ፡— ወንድሜ ፡ ሆይ ÷ አይሆንም ፤ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ አይገባምና ፡ አታሳፍረኝ ፤ ይህንም ፡ ነውረኛ ፡ ሥራ ፡ አታድርግ ። ፲፫ እኔም ፡ ነውሬን ፡ ወዴት ፡ ልሸከም ? አንተም ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ከምናምንቴዎች ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ትሆናለህ ፤ አንግዲህስ ፡ ለንጉሡ ፡ ንገረው ÷ እኔንም ፡ አይነሣህም ፡ አለችው ። ፲፬ ቃልዋን ፡ ግን ፡ አልሰማም ፤ ከእርስዋም ፡ ይልቅ ፡ ብርቱ ፡ ነበረና ፡ በግድ ፡ አስነወራት ÷ ከእርስዋም ፡ ጋር ፡ ተኛ ።

፲፭ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ አምኖን ፡ ፈጽሞ ፡ ጠላት ፤ አስቀድሞም ፡ ከወደዳት ፡ ውድ ፡ ይልቅ ፡ በኋላ ፡ የጠላት ፡ ጥል ፡ በለጠ ። አምኖንም ፡— ተነሥተሽ ፡ ሂጂ ፡ አላት ። ፲፮ እርስዋም ፡— አይሆንም ፤ ቀድሞ ፡ ከሠራኸው ፡ ክፋት ፡ ይልቅ ፡ እኔን ፡ በማውጣትህ ፡ የበለጠ ፡ ክፋት ፡ ትሠራለህ ፡ አለችው ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ አልሰማትም ። ፲፯ የሚያገለግለውንም ፡ ብላቴና ፡ ጠርቶ ፡— ይህችን ፡ ሴት ፡ ከፊቴ ፡ አስወጥተህ ፡ በሩን ፡ ዝጋበት ፡ አለው ። ፲፰ ብዙ ፡ ኅብር ፡ ያለውንም ፡ ልብስ ፡ ለብሳ ፡ ነበር ÷ እንዲህ ፡ ያለውን ፡ ልብስ ፡ የንጉሡ ፡ ልጆች ፡ ደናግሉ ፡ ይለብሱ ፡ ነበርና ፤ አገልጋዩም ፡ አስወጥቶ ፡ በሩን ፡ ዘጋበት ። ፲፱ ትዕማርም ፡ በራስዋ ፡ ላይ ፡ አመድ ፡ ነስንሳ ÷ ብዙ ፡ ኅብርም ፡ ያለውን ፡ ልብስዋን ፡ ተርትራ ÷ እጅዋንም ፡ በራስዋ ፡ ላይ ፡ ጭና ፡ እየጮኸች ፡ ሄደች ።

፳ ወንድምዋም ፡ አቤሴሎም ፡— ወንድምሽ ፡ አምኖን ፡ ከአንቺ ፡ ጋር ፡ ነበረን? እኅቴ ፡ ሆይ ÷ አሁን ፡ ግን ፡ ዝም ፡ በዪ ፤ ወንድምሽ ፡ ነው ! ይህን ፡ ነገር ፡ በልብሽ ፡ አትያዢው ፡ አላት ። ትዕማርም ፡ በወንድምዋ ፡ በአቤሴሎም ፡ ቤት ፡ ብቻዋን ፡ ተቀመጠች ። ፳፩ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የበኵር ፡ ልጁ ፡ ነበረና ፡ ስለ ፡ ወደደው ፡ የልጁን ፡ የአምኖን ፡ ነፍስ ፡ አላሳዘነም ። ፳፪ አቤሴሎምም ፡ እኅቱን ፡ ትዕማርን ፡ ስላሳፈራት ፡ አምኖንን ፡ ጠልቶታልና ፡ አቤሴሎም ፡ አምኖንን ፡ ክፉም ፡ ሆነ ፡ መልካምም ፡ አልተናገረውም ።

፳፫ ከሁለት ፡ ዓመትም ፡ በኋላ ፡ አቤሴሎም ፡ በኤፍሬም ፡ አቅራቢያ ፡ ባለችው ፡ በቤላሶር ፡ በጎቹን ፡ አሸለተ ፤ አቤሴሎምም ፡ የንጉሡን ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ጠራ ። ፳፬ አቤሴሎምም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ መጥቶ ፡— እነሆ ÷ ባሪያህ ፡ በጎቹን ፡ ያሸልታል ፤ ንጉሡና ፡ ሎሌዎቹ ፡ ከባሪያህ ፡ ጋር ፡ ይሂዱ ፡ አለው ። ፳፭ ንጉሡም ፡ አቤሴሎምን ፡— ልጄ ፡ ሆይ ÷ እንከብድብሃለንና ፡ ሁላችን ፡ እንመጣ ፡ ዘንድ ፡ አይሆንም ፡ አለው ። የግድም ፡ አለው ÷ እርሱ ፡ ግን ፡ መረቀው ፡ እንጂ ፡ ለመሄድ ፡ እንቢ ፡ አለ ። ፳፮ አቤሴሎምም ፡— አንተ ፡ እንቢ ፡ ካልህ ፡ ወንድሜ ፡ አምኖን ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ እንዲሄድ ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለ ። ንጉሡም ፡— ከአንተ ፡ ጋር ፡ ለምን ፡ ይሄዳል ? አለው ። ፳፯ አቤሴሎምም ፡ የግድ ፡ አለው ÷ አምኖንንና ፡ የንጉሡንም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሰደደ ። ፳፰ አቤሴሎምም ፡ እንደ ፡ ንጉሥ ፡ ግብዣ ፡ ያለ ፡ ግብዣ ፡ አደረገ ፤ አቤሴሎምም ፡ አገልጋዮቹን ፡— አምኖን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ጠጥቶ ፡ ልቡን ፡ ደስ ፡ ባለው ፡ ጊዜ ፡ እዩ ፡— አምኖንን ፡ ግደሉ ፡ በልኋችሁም ፡ ጊዜ ፡ ግደሉት ÷ አትፍሩም ፤ ያዘዝኋችሁም ፡ እኔ ፡ ነኝና ፡ በርቱ ፡ ጽኑም ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ። ፳፱ የአቤሴሎምም ፡ አገልጋዮች ፡ አቤሴሎም ፡ እንዳዘዛቸው ፡ በአምኖን ፡ ላይ ፡ አደረጉበት ። የንጉሡም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ተነሥተው ፡ በየበቅሎቻቸው ፡ ተቀምጠው ፡ ሸሹ ።

፴ ገናም ፡ በመንገድ ፡ ሲሄዱ ፡ ለዳዊት ፡— አቤሴሎም ፡ የንጉሡን ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ገድሎአል ÷ ከእነርሱም ፡ አንድ ፡ አልቀረም ፡ የሚል ፡ ወሬ ፡ መጣለት ። ፴፩ ንጉሡም ፡ ተነሥቶ ፡ ልብሱን ፡ ቀደደ ÷ በምድር ፡ ላይም ፡ ወደቀ ፤ ባሪያዎቹም ፡ ሁሉ ፡ ልብሳቸውን ፡ ቀድደው ፡ በአጠገቡ ፡ ቆሙ ። ፴፪ የዳዊትም ፡ ወንድም ፡ የሳምዓ ፡ ልጅ ፡ ኢዮናዳብ ፡— ጌታዬ ፡ ጕልማሶቹ ፡ የንጉሡ ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡ አያስብ ፤ እኅቱን ፡ ትዕማርን ፡ በግድ ፡ ካስነወራት ፡ ጀምሮ ፡ በአቤሴሎም ፡ ዘንድ ፡ የተቈረጠ ፡ ነገር ፡ ነበረና ፡ የሞተ ፡ አምኖን ፡ ብቻ ፡ ነው ። ፴፫ አሁንም ፡ የሞተ ፡ አምኖን ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የንጉሥ ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ሞቱ ፡ ብሎ ፡ ጌታዬ ፡ ንጉሡ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ በልቡ ፡ አያኑር ፡ አለው ።

፴፬ አቤሴሎምም ፡ ኰበለለ ። ጕበኛውም ፡ ጕልማሳ ፡ ዓይኑን ፡ ከፍ ፡ አደረገ ÷ እነሆም ÷ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ በኋላው ፡ በተራራው ፡ አጠገብ ፡ በመንገድ ፡ ሲመጡ ፡ አየ ። ፴፭ ኢዮናዳብም ፡ ንጉሡን ፡— እነሆ ÷ የንጉሡ ፡ ልጆች ፡ መጥተዋል ፤ ባሪያህ ፡ እንዳለው ፡ እንዲሁ ፡ ሆኖአል ፡ አለው ። ፴፮ ተናግሮም ፡ በጨረሰ ፡ ጊዜ ÷ እነሆ ÷ ወዲያው ፡ የንጉሥ ፡ ልጆች ፡ ገቡ ÷ ድምፃቸውንም ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡ አለቀሱ ፤ ደግሞ ፡ ንጉሡና ፡ ባሪያዎቹ ፡ ሁሉ ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ልቅሶ ፡ አለቀሱ ።

፴፯ አቤሴሎም ፡ ግን ፡ ኰብልሎ ፡ ወደ ፡ ጌሹር ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ዓሚሁድ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ተልማይ ፡ ሄደ ። ዳዊትም ፡ ሁልጊዜ ፡ ለልጁ ፡ ያለቅስ ፡ ነበር ። ፴፰ አቤሴሎም ፡ ኰብልሎ ፡ ወደ ፡ ጌሹር ፡ ሄደ ÷ በዚያም ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ ተቀመጠ ። ፴፱ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ስለ ፡ አምኖን ፡ ሞት ፡ ተጽናንቶ ፡ ወደ ፡ አቤሴሎም ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ እጅግ ፡ ናፈቀ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ የጽሩያም ፡ ልጅ ፡ ኢዮአብ ፡ የንጉሡ ፡ ልብ ፡ ወደ ፡ አቤሴሎም ፡ እንዳዘነበለ ፡ አወቀ ። ፪ ኢዮአብም ፡ ወደ ፡ ቴቁሔ ፡ ልኮ ፡ ከዚያ ፡ ብልሃተኛ ፡

ሴት ፡ አስመጣና ፡— አልቅሺ ፥ የኀዘንም ፡
ልብስ ፡ ልበሺ ፥ ዘይትም ፡ አትቀቢ ፥ ስለ ፡ ሞተ ፡
ሰውም ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ እንደምታለቅሺ ፡ ሁኚ ፤
፫ ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ገብተሽ ፡ እንዲህ ፡ ያለውን ፡
ቃል ፡ ንገሪው ፡ አላት ፤ ኢዮአብም ፡ ቃሉን ፡
በእርስዋ ፡ አፍ ፡ አደረገ ።

፬ እንዲሁም ፡ የቴቁሔይቱ ፡ ሴት ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡
ገብታ ፡ በግምባርዋ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ወደቀች ፥
እጅ ፡ ነሥታም ፡— ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ አድነኝ ፡
፭ አለች ። ንጉሡም ፡— ምን ፡ ሆነሻል ? አላት ።
እርስዋም ፡ መልሳ ፡ አለች ፡— በእውነት ፡ እኔ ፡
፮ ባሌ ፡ የሞተብኝ ፡ ባልቴት ፡ ሴት ፡ ነኝ ። ለእኔም ፡
ለባሪያህ ፡ ሁለት ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ ነበሩኝ ፥
በሜዳም ፡ ተጣሉ ፤ የሚገላግላቸውም ፡ አልነ
በረም ፥ አንዱም ፡ ሌላውን ፡ መትቶ ፡ ገደለው ።
፯ እነሆም ፥ ዘመዶች ፡ ሁሉ ፡ በባሪያህ ፡ ላይ ፡ ተነ
ሥተው ፡— ስለ ፡ ገደለው ፡ ስለ ፡ ወንድሙ ፡
ነፍስ ፡ እንገድለው ፡ ዘንድ ፡ ወንድሙን ፡ የገደ
ለውን ፡ አውጪ ፡ አሉኝ ፤ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡
ወራሹን ፡ የቀረውን ፡ መብራቴን ፡ ያጠፋሉ ፥
የባሌን ፡ ስምና ፡ ዘርም ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ አያስ
ቀሩም ።

፰ ንጉሡም ፡ ሴቲቱን ፡— ወደ ፡ ቤትሽ ፡ ሂጂ ፥
፱ እኔም ፡ ስለ ፡ አንቺ ፡ አዝዛለሁ ፡ አላት ። የቴቁ
ሔይቱም ፡ ሴት ፡ ንጉሡን ፡— ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡
ሆይ ፥ ኃጢአቱ ፡ በእኔና ፡ በአባቴ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡
ይሁን ፤ ንጉሡና ፡ ዙፋኑ ፡ ንጹሕ ፡ ይሁን ፡ አለ
፲ ችው ። ንጉሡም ፡— የሚናገርሽን ፡ አምጪ
ልኝ ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ደግሞ ፡ አይነካሽም ፡
፲፩ አለ ። እርስዋም ፡— ደም ፡ ተበቃዮችም ፡ ከእ
ንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ እንዳያጠፉ ፡ ልጄንም ፡ እንዳ
ይገድሉ ፥ ንጉሡ ፡ አምላኩን ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ ያስብ ፡ አለች ። እርሱም ፡— ሕያው ፡ እግ
ዚአብሔርን ! ከልጅሽ ፡ አንድ ፡ ጠጕር ፡ በም
ድር ፡ ላይ ፡ አይወድቅም ፡ አለ ።

፲፪ ሴቲቱም ፡— እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ለጌታዬ ፡ ለንጉሥ ፡
አንድ ፡ ቃል ፡ ልናገር ፡ አለች ፤ እርሱም ፡—
፲፫ ተናገሪ ፡ አለ ። ሴቲቱም ፡ አለች ፡— በእግዚአ
ብሔር ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ስለ ፡
ምን ፡ አሰብህ ? ንጉሡ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ተናግሮ
አልና ፡ ያሳደደውን ፡ ስላላስመለሰ ፡ በደለኛ ፡
፲፬ ነው ። ሁላችን ፡ እንሞታለን ፥ በምድርም ፡
ላይ ፡ እንደ ፡ ፈሰሰና ፡ እንደማይመለስ ፡ ውኃ ፡
ነን ፤ እግዚአብሔርም ፡ የነፍስን ፡ ጥፋት ፡ አይ
ወድድም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ የተጣለ ፡ ሰው ፡ ፈጽሞ ፡
፲፭ እንዳይጠፋ ፡ በምክሩ ፡ ያስባል ። አሁንም ፡
ሕዝቡ ፡ ስለሚያስፈራኝ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ለጌ
ታዬ ፡ ለንጉሥ ፡ እነግረው ፡ ዘንድ ፡ መጥቻለሁ ፤
እኔም ፡ ባሪያህ ፡— ምናልባት ፡ የእኔን ፡ የባሪያ
ውን ፡ ልመና ፡ ንጉሡ ፡ ያደርግልኝ ፡ እንደ ፡
፲፮ ሆነ ፡ ለንጉሡ ፡ ልናገር ፤ እርስዋንና ፡ ልጅዋን ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ርስት ፡ ያጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡
ከሚሻ ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ ንጉሡ ፡
፲፯ ባሪያውን ፡ ይሰማል ፡ አልሁ ። እኔም ፡ ባሪያህ ፡—
መልካሙንና ፡ ክፉውን ፡ ነገር ፡ ለመስማት ፡
ንጉሡ ፡ ጌታዬ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መል
አክ ፡ ነውና ፡ የጌታዬ ፡ የንጉሡ ፡ ቃል ፡ ያጽናና
ኛል ፤ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡
ጋር ፡ ይሁን ፡ አልሁ ።

፲፰ ንጉሡም ፡ ለሴቲቱ ፡ መልሶ ፡— የምጠይቅ
ሽን ፡ ነገር ፡ አትሰውሪኝ ፡ አላት ። ሴቲቱም ፡—
፲፱ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ይናገር ፡ አለች ። ንጉሡም ፡—
በዚህ ፡ ሁሉ ፡ የኢዮአብ ፡ እጅ ፡ ከአንቺ ፡ ጋር ፡
ነውን ? አላት ። ሴቲቱም ፡ መልሳ ፡— ጌታዬ ፡
ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ በሕያው ፡ ነፍስህ ፡ እምላለሁ !
ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ከተናገረው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡
ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ ሊል ፡ የሚችል ፡ የለም ፤
ባሪያህ ፡ ኢዮአብ ፡ አዝዞኛል ፥ ይህንም ፡ ቃል ፡
፳ ሁሉ ፡ በባሪያህ ፡ አፍ ፡ አደረገው ። ባሪያህ ፡
ኢዮአብ ፡ የዚህ ፡ ነገር ፡ መልክ ፡ እንዲለውጥ ፡
አደረገ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ መል
አክ ፡ ጠቢብ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ አንተም ፡ ጌታዬ ፡
በምድር ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ታውቅ ፡
ዘንድ ፡ ጠቢብ ፡ ነህ ፡ አለች ።

፳፩ ንጉሡም ፡ ኢዮአብን ፡— እነሆ ፥ ይህን ፡
ነገር ፡ አድርጌአለሁ ፤ እንግዲህ ፡ ሂድና ፡ ብላ
ቴናውን ፡ አቤሴሎምን ፡ መልሰው ፡ አለው ።
፳፪ ኢዮአብም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በግምባሩ ፡ ወድቆ ፡
እጅ ፡ ነሣ ፥ ንጉሡንም ፡ ባረከ ፤ ኢዮአብም ፡—
ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ የባሪያህን ፡ ነገር ፡ አድ
ርገሃልና ፡ በዓይንህ ፡ ፊት ፡ ሞገስ ፡ እንዳገኘ ፡
፳፫ ባሪያህ ፡ ዛሬ ፡ አወቀ ፡ አለ ። ኢዮአብም ፡ ተነ
ሥቶ ፡ ወደ ፡ ጌሹር ፡ ሄደ ፥ አቤሴሎምንም ፡
፳፬ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ይዞ ፡ መጣ ። ንጉሡም ፡—
ወደ ፡ ቤቱ ፡ ይሂድ ፡ እንጂ ፡ ፊቴን ፡ እንዳያይ ፡
አለ ፤ አቤሴሎምም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ፥ የንጉ
ሡንም ፡ ፊት ፡ አላየም ።

፳፭ በእስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ አቤሴ
ሎም ፡ በውበቱ ፡ የተመሰገነ ፡ ሰው ፡ አልነበ
ረም ፤ ከእግሩ ፡ እስከ ፡ ራሱ ፡ ድረስ ፡ነውር ፡
፳፮ አልነበረበትም ። ጠጕሩም ፡ ይከብደው ፡ ነበ
ርና ፡ በዓመት ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ይቈርጠው ፡ ነበር ፤
ሲቈረጥም ፡ የራሱ ፡ ጠጕር ፡ በንጉሥ ፡ ሚዛን ፡
ሁለት ፡ መቶ ፡ ሰቅል ፡ ያህል ፡ ይመዘን ፡ ነበር ።
፳፯ ለአቤሴሎምም ፡ ሦስት ፡ ወንዶች ፡ ልጆችና ፡
አንዲት ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ተወለዱለት ፤ የሴቲቱም ፡
ልጅ ፡ ስም ፡ ትዕማር ፡ ነበረ ፥ እርስዋም ፡ የተዋ
በች ፡ ሴት ፡ ነበረች ።

፳፰ አቤሴሎምም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡
ሙሉ ፡ የንጉሡን ፡ ፊት ፡ ሳያይ ፡ ተቀመጠ ።
፳፱ አቤሴሎምም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ይልከው ፡ ዘንድ ፡
ወደ ፡ ኢዮአብ ፡ ላከ ፥ ወደ ፡ እርሱም ፡ ሊመጣ ፡
አልወደደም ፤ ሁለተኛም ፡ ላከበት ፥ ሊመጣ ፡
፴ ግን ፡ አልወደደም ። ባሪያዎቹንም ፡— በእር
ሻዬ ፡ አጠገብ ፡ ያለውን ፡ የኢዮአብን ፡ እርሻ ፡
እዩ ፥ በዚያም ፡ ገብስ ፡ አለው ፤ ሂዱችሁ ፡ በእ
ሳት ፡ አቃጥሉት ፡ አላቸው ። የአቤሴሎምም ፡
፴፩ ባሪያዎች ፡ እርሻውን ፡ አቃጠሉት ። ኢዮአ

ብም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ አቤሴሎም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡
መጣና ፡— ባሪያዎችህ ፡ እርሻዬን ፡ ስለ ፡ ምን ፡
፴፪ አቃጠሉት ? አለው ። አቤሴሎምም ፡ ኢዮአ
ብን ፡ መልሶ ፡— ከጌሹር ፡ ለምን ፡ መጣሁ ? በዚ
ያም ፡ ተቀምጬ ፡ ብሆን ፡ ይሻለኝ ፡ ነበር ፡ ብለህ ፡
እንድትነግረው ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ እልክህ ፡ ዘንድ ፡
ወደ ፡ እኔ ፡ ጠራሁህ ፤ አሁንም ፡ የንጉሡን ፡
ፊት ፡ ልይ ÷ ኃጢአት ፡ ቢሆንብኝ ፡ ይግደለኝ ፡
፴፫ አለው ። ኢዮአብም ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡ መጥቶ ፡
ነገረው ፤ አቤሴሎምንም ፡ ጠራው ÷ ወደ ፡ ንጉ
ሡም ፡ ገብቶ ፡ በንጉሥ ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ምድር ፡
በግምባሩ ፡ ተደፋ ፤ ንጉሡም ፡ አቤሴሎምን ፡
ሳመው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ አቤሴሎም ፡ ሰረገላና ፡ ፈረ
ሶች ÷ በፊቱም ፡ የሚሮጡ ፡ አምሳ ፡ ሰዎች ፡
፪ አዘጋጀ ። አቤሴሎምም ፡ በማለዳ ፡ ተነሥቶ ፡
በበሩ ፡ አደባባይ ፡ ይቆም ፡ ነበር ፤ አቤሴሎ
ምም ፡ ከንጉሥ ፡ ለማስፈረድ ፡ ጉዳይ ፡ የነበረ
ውን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ እየጠራ ፡— አንተ ፡
ከወዴት ፡ ከተማ ፡ ነህ ? ብሎ ፡ ይጠይቅ ፡ ነበር ።
እርሱም ፡— እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ከእስራኤል ፡ ነገድ ፡
፫ ከአንዲቱ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ ይመልስ ፡ ነበር ። አቤ
ሴሎምም ፡— ነገርህ ፡ እውነትና ፡ ቅን ፡ ነው ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ከንጉሥ ፡ ታዝዞ ፡ የሚሰማህ ፡ የለም ፡
፬ ይለው ፡ ነበር ። አቤሴሎምም ፡— ነገርና ፡ ክር
ክር ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡
ቅንም ፡ ፍርድ ፡ እፈርድለት ፡ ዘንድ ፡ በአገር ፡
ላይ ፡ ፈራጅ ፡ አድርጎ ፡ ማን ፡ በሾመኝ ? ይል ፡
፭ ነበር ። ሰውም ፡ እጅ ፡ ሊነሣው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡
በቀረበ ፡ ጊዜ ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡ ይይዝና ፡ ይስ
፮ መው ፡ ነበር ። እንዲሁም ፡ አቤሴሎም ፡ ከን
ጉሥ ፡ ፍርድ ፡ ሊሰማ ፡ ከእስራኤል ፡ ዘንድ ፡
በሚመጣ ፡ ሁሉ ፡ ያደርግ ፡ ነበር ፤ አቤሴሎ
ምም ፡ የእስራኤልን ፡ ሰዎች ፡ ልብ ፡ ሰረቀ ።
፯ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ከአራት ፡ ዓመት ፡ በኋላ ፡
አቤሴሎም ፡ ንጉሡን ፡— ለእግዚአብሔር ፡ የተ
ሳልሁትን ፡ ስእለት ፡ ለመስጠት ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ÷
፰ እባክህ ÷ ልሂድ ። እኔ ፡ ባሪያህ ፡ በሶርያ ፡ ጌሹር ፡
ሳለሁ ፡— እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
ቢመልሰኝ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሥዋዕት ፡ አቀ
ርባለሁ ፡ ብዬ ፡ ስእለት ፡ ተስዬ ፡ ነበር ፡ አለው ።
፱ ንጉሡም ፡— በደኅና ፡ ሂድ ፡ አለው ፤ ተነሥቶም ፡
፲ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ ሄደ ። አቤሴሎምም ፡ በእስራ
ኤል ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡— የቀንደ ፡ መለከት ፡ ድምፅ ፡
በሰማችሁ ፡ ጊዜ ፡— አቤሴሎም ፡ በኬብሮን ፡
፲፩ ነገሠ ፡ በሉ ፡ የሚሉ ፡ ጒበኞች ፡ ላከ ። የተጠሩ
ትም ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ከአቤሴሎም ፡
ጋር ፡ በየዋህነት ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ሄዱ ፤ የሚ
ሆነውንም ፡ ነገር ፡ ከቶ ፡ አያውቁም ፡ ነበር ።
፲፪ አቤሴሎምም ፡ የዳዊት ፡ መካር ፡ የነበረውን ፡
የጊሎ ፡ ሰው ፡ አኪጦፌልን ፡ ከከተማው ፡ ከጊሎ ፡
መሥዋዕት ፡ በሚያቀርብበት ፡ ጊዜ ፡ አስጠ
ራው ። ሴራውም ፡ ጽኑ ፡ ሆነ ፤ ከአቤሴሎምም ፡
ጋር ፡ ያለው ፡ ሕዝብ ፡ እየበዛ ፡ ሄደ ።
፲፫ ለዳዊትም ፡— የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ልብ ፡ ከአ
ቤሴሎም ፡ ጋር ፡ ሆኖአል ፡ የሚል ፡ ወሬኛ ፡ መጣ
፲፬ ለት ። ዳዊትም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በኢየሩሳሌም ፡
ያሉትን ፡ ባሪያዎቹን ፡ ሁሉ ፡— ተነሡ ÷ እንሽሽ ፤
ያለዚያ ፡ ከአቤሴሎም ፡ እጅ ፡ የሚድን ፡ ከእኛ ፡
የለምና ፤ መጥቶም ፡ እንዳይዘን ÷ ክፉም ፡ እን
ዳያመጣብን ፡ ከተማይቱንም ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡
እንዳይመታ ፡ ፈጥናችሁ ፡ እንሂድ ፡ አላቸው ።
፲፭ የንጉሡም ፡ ባሪያዎች ፡ ንጉሡን ፡— እነሆ ÷
ጌታችን ፡ ንጉሡ ፡ የመረጠውን ፡ ሁሉ ፡ እኛ ፡
ባሪያዎችህ ፡ እሺ ፡ ብለን ፡ እናደርጋለን ፡ አሉት ።
፲፮ ንጉሡም ፡ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ቤተ ፡ ሰቡ ፡ ሁሉ ፡
ወጡ ፤ ንጉሡም ፡ አሥሩን ፡ ሴቶች ፡ ቁባቶቹን ፡
፲፯ ቤቱን ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ተወ ። ንጉሡም ፡
ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ወጡ ÷ በቤ
፲፰ ትሜርሐቅም ፡ ቆሙ ። ባሪያዎቹም ፡ ሁሉ ፡
በፊቱ ፡ አለፉ ፤ ከሊታውያንና ፡ ፈሊታውያ
ንም ፡ ሁሉ ÷ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ከጌት ፡ የመ
ጡት ፡ ስድስት ፡ መቶው ፡ ጌታውያን ፡ ሁሉ ፡
በንጉሡ ፡ ፊት ፡ አለፉ ።
፲፱ ንጉሡም የጌት ፡ ሰው ፡ ኢታይን ፡— ከእኛ ፡
ጋር ፡ ለምን ፡ መጣህ ? አንተ ፡ ከስፍራህ ፡ የመ
ጣህ ፡ እንግዳና ፡ ስደተኛ ፡ ነህና ፡ ተመለስ ÷
፳ ከንጉሡም ፡ ጋር ፡ ተቀመጥ ። የመጣኸው ፡ ትና
ንት ፡ ነው ፤ ዛሬ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ላዟርህን ? እኔ ፡
ወደምሄድበት ፡ እሄዳለሁ ! አንተ ፡ ግን ፡ ተመ
ለስ ÷ ወንድሞችህንም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ውሰድ ÷
እግዚአብሔርም ፡ ምሕረቱንና ፡ እውነቱን ፡
፳፩ ያድርግልህ ፡ አለው ። ኢታይም ፡ ለንጉሡ ፡
መልሶ ፡— ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! በጌታ
ዬም ፡ በንጉሡ ፡ ሕይወት ፡ እምላለሁ ! በእው
ነት ፡ ጌታዬ ፡ ባለበት ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ÷ በሞትም ፡
ቢሆን ፡ በሕይወትም ÷ በዚያ ፡ ደግሞ ፡ እኔ ፡ ባሪ
፳፪ ያህ ፡ እሆናለሁ ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ ኢታይን ፡—
ሂድ ፡ ተሻገር ፡ አለው ፤ የጌት ፡ ሰው ፡ ኢታ
ይና ፡ ሰዎቹም ፡ ሁሉ ÷ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነ
፳፫ በሩት ፡ ሕፃናት ፡ ሁሉ ፡ ተሻገሩ ። በአገርም ፡
የነበሩት ፡ ሁሉ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ አለቀሱ ፤
ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ተሻገሩ ÷ ንጉሡም ፡ ደግሞ ፡
የቄድሮንን ፡ ፈፋ ፡ ተሻገረ ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ መንገድ ፡ ተሻገሩ ።
፳፬ እነሆም ÷ ደግሞ ፡ ሳዶቅ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡
ሌዋውያን ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
ኪዳን ፡ ታቦት ፡ ተሸክመው ፡ መጡ ፤ የእግዚአብ
ሔርንም ፡ ታቦት ፡ አስቀመጡ ÷ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡
ከከተማይቱ ፡ ፈጽሞ ፡ እስኪያልፉ ፡ ድረስ ፡ አብያ
፳፭ ታር ፡ ወጣ ። ንጉሡም ፡ ሳዶቅን ፡— የእግዚአብሔ
ርን ፡ ታቦት ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ መልስ ፤ በእግዚአ
ብሔር ፡ ዓይን ፡ ሞገስ ፡ አግኝቼ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ÷
መልሶ ፡ እርሱንና ፡ ማደሪያውን ፡ ያሳየኛል ፤
፳፮ ነገር ፡ ግን ፡— አልወድድህም ፡ ቢለኝ ÷ እነሆኝ ÷
ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡ ያድርግብኝ ፡ አለው ።

፳፯ ንጉሡም ፡ ደግሞ ፡ ከህኑን ፡ ሳዶቅን ፡— እነሆ ÷
አንተና ፡ ልጅህ ፡ አኪ.ማአስ ፡ የአብያታርም ፡
ልጅ ፡ ዮናታን ፡ ሁለቱ ፡ ልጆቻችሁ ፡ በደኅና ፡
፳፰ ወደ ፡ ከተማ ፡ ተመለሱ ። እኔም ÷ እነሆ ÷ ከእ
ናንተ ፡ ዘንድ ፡ ወሬ ፡ እስኪ.መጣልኝ ፡ ድረስ ፡
በምድረ ፡ በዳው ፡ መሻገርያ ፡ እቆያለሁ ፡ አለው ።
፳፱ ሳዶቅም ፡ አብያታርም ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ታቦት ፡ ወደ ፡ ኢ.የሩሳሌም ፡ መለሱት ÷ በዚ.ያም ፡
ተቀመጡ ።

፴ ዳዊትም ፡ ተከናንበ ፡ ያለ ፡ ጫማ ፡ እያለቀሰ ፡
ወደ ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡ ዐቀበት ፡ ወጣ ፤ ከእርሱም ፡
ጋር ፡ የነበሩት ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ተከናንበው ፡
፴፩ እያለቀሱ ፡ ወጡ ። አኪ.ጦፌል ፡ ከአቤሴሎም ፡
ጋር ፡ በሴራ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ለዳዊት ፡
ነገሩት ፤ ዳዊትም ፡— አቤቱ ÷ የአኪ.ጦፌልን ፡
ምክር ፡ ስንፍና ፡ አድርገህ ፡ እንድትለውጥ ፡
፴፪ እለምንሃለሁ ፡ አለ ። ዳዊትም ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ወደ ፡ ሰገደበት ፡ ወደ ፡ ተራራው ፡ ራስ ፡ በመጣ ፡
ጊዜ ÷ አርካዊው ፡ ኩሲ ፡ ልብሱን ፡ ቀድዶ ፡ በራ
ሱም ፡ ላይ ፡ ትቢ.ያ ፡ ነስንሶ ፡ ሊ.ገናኘው ፡ መጣ ።
፴፫ ዳዊትም ፡ አለው ፡— ከእኔ ፡ ጋር ፡ ብትመጣ ፡
፴፬ ትከብደኛለህ ፤ ወደ ፡ ከተማ ፡ ግን ፡ ተመልሰህ ፡
ለአቤሴሎም ፡— ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ ባሪያ ፡ እሆንሃ
ለሁ ፤ አስቀድሞ ፡ ለአባትህ ፡ ባሪያ ፡ እንደ ፡
ነበርሁ ፡ እንዲሁ ፡ አሁን ፡ ለአንተ ፡ ባሪያ ፡ እሆ
ንሃለሁ ፡ ብትለው ፡ የአኪ.ጦፌልን ፡ ምክር ፡
፴፭ ከንቱ ፡ ታደርግልኛለህ ። ከህናቱ ፡ ሳዶቅና ፡
አብያታርም ፡ በዚ.ያ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አይደሉ
ምን ? ከንጉሡ ፡ ቤትም ፡ የምትሰማውን ፡ ነገር ፡
ሁሉ ፡ ለካህናቱ ፡ ለሳዶቅና ፡ ለአብያታር ፡ ንገሩ
፴፮ ቸው ። እነሆ ÷ የሳዶቅ ፡ ልጅ ፡ አኪ.ማአስና ፡
የአብያታር ፡ ልጅ ፡ ዮናታን ፡ ልጆቻቸው ፡ በዚ.ያ ፡
ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ አሉ ፤ የምትሰሙትን ፡ ሁሉ ፡
፴፯ በእነርሱ ፡ እጅ ፡ ላኩልኝ ። የዳዊትም ፡ ወዳጅ ፡
ኩሲ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ መጣ ፤ አቤሴሎምም ፡
ደግሞ ፡ ወደ ፡ ኢ.የሩሳሌም ፡ ገባ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ ዳዊትም ፡ ከተራራው ፡ ራስ ፡ ጥቂት ፡ ፈቀቅ ፡
ባለ ፡ ጊዜ ፡ የሜምፊቦስቴ ፡ ባሪያ ፡ ሲ.ባ ፡ ሁለት ፡
መቶ ፡ እንጀራ ÷ አንድ ፡ መቶም ፡ ዘለላ ፡ ዘቢ.ብ ÷
አንድ ፡ መቶም ፡ በለስ ÷ አንድ ፡ አቁማዳም ፡
ወይን ፡ ጠጅ ፡ የተጫኑ ፡ ሁለት ፡ አህዮች ፡ እየ
፪ ነዳ ፡ ተገናኘው ። ንጉሡም ፡ ሲ.ባን ፡— ይህ ፡
ምንድር ፡ ነው ? አለው ። ሲ.ባም ፡— አህዮቹ ፡
የንጉሥ ፡ ቤተ ፡ ሰቦች ፡ ይቀመጡባቸው ፡
ዘንድ ÷ እንጀራውና ፡ በለሱ ፡ ብላቴኖቹ ፡ ይበ
ሉት ፡ ዘንድ ÷ የወይን ፡ ጠጁም ፡ በበረሀ ፡ የሚደ
፫ ክሙት ፡ ይጠጡት ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ አለ ። ንጉ
ሡም ፡— የጌታህ ፡ ልጅ ፡ ወዴት ፡ ነው ? አለ ።
ሲ.ባም ፡ ንጉሡን ፡— እነሆ ፡— የእስራኤል ፡
ቤት ፡ ዛሬ ፡ የአባቴን ፡ መንግሥት ፡ ይመልስል
ኛል ፡ ብሎ ፡ በኢ.የሩሳሌም ፡ ተቀምጦአል ፡
፬ አለው ። ንጉሡም ፡ ሲ.ባን ፡— እነሆ ÷ ለሜም
ፊቦስቴ ፡ የነበረው ፡ ሁሉ ፡ ለአንተ ፡ ይሁን ፡
አለው ። ሲ.ባም ፡— እጅ ፡ እነሣለሁ ፤ ጌታዬ ፡
ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ በፊትህ ፡ ሞገስ ፡ ላግኝ ፡ አለ ።

፭ ንጉሡ ፡ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ ብራቂም ፡ መጣ ፤
እነሆም ÷ ሳሚ ፡ የሚባል ፡ የጌራ ፡ ልጅ ፡ ከሳ
ኦል ፡ ቤተ ፡ ዘመድ ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ከዚ.ያ ፡
፮ ወጣ ÷ እየሄደም ፡ ይረግመው ፡ ነበር ። ወደ ፡
ዳዊትና ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ባሪያ
ዎችም ፡ ድንጋይ ፡ ይወረውር ፡ ነበር ፤ በንጉሡም ፡
ቀኝና ፡ ግራ ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉና ፡ ኃያላኑ ፡ ሁሉ ፡
፯ ነበሩ ። ሳሚም ፡ ሲረግም ፡— ሂድ ÷ አንተ ፡ የደም ፡
፰ ሰው ÷ ምናምንቴ ÷ ሂድ ። በፋንታው ፡ ነግሥ
ሃልና ፡ እግዚአብሔር ፡ የሳኦልን ፡ ቤት ፡ ደም ፡
ሁሉ ፡ መለሰብህ ፤ እግዚአብሔርም ፡ መንግሥ
ትን ፡ ለልጅህ ፡ ለአቤሴሎም ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡
ሰጥቶታል ፤ እነሆም ÷ አንተ ፡ የደም ፡ ሰው ፡
ነህና ፡ በመከራ ፡ ተይዘሃል ፡ አለ ።

፱ የጽሩያም ፡ ልጅ ፡ አቢ.ሳ ፡ ንጉሡን ፡— ይህ ፡
የሞተ ፡ ውሻ ፡ ጌታዬን ፡ ንጉሡን ፡ ስለ ፡ ምን ፡
ይረግማል ? ልሂድና ፡ ራሱን ፡ ልቍረጠው ፡
፲ አለው ። ንጉሡም ፡— እናንተ ፡ የጽሩያ ፡
ልጆች ÷ እኔ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አለኝ ? እግ
ዚአብሔር ፡— ዳዊትን ፡ ስደበው ፡ ብሎ ፡ አዝዞ
ታልና ፡ ይርገመኝ ፤ ለምንስ ፡ እንዲህ ፡ ታደርጋ
፲፩ ለህ ? የሚለው ፡ ማን ፡ ነው ? አለ ። ዳዊትም ፡
አቢ.ሳንና ፡ ባሪያዎቹን ፡ ሁሉ ፡— እነሆ ÷ ከወ
ገቤ ፡ የወጣው ፡ ልጄ ፡ ነፍሴን ፡ ይሻል ፤ ይል
ቁንስ ፡ ይህ ፡ የብንያም ፡ ልጅ ፡ እንዴት ፡ ነዋ ?
እግዚአብሔር ፡ አዝዞታልና ፡ ተዉት ÷ ይርገ
፲፪ መኝ ። ምናልባት ፡ በዚህ ፡ ቀን ፡ መከራዬን ፡
አይቶ ፡ ስለ ፡ እርግማኑ ፡ መልካም ፡ ይመልስል
፲፫ ኛል ፡ አላቸው ። ዳዊትና ፡ ሰዎቹም ፡ በመንገድ ፡
ይሄዱ ፡ ነበር ፤ ሳሚም ፡ በተራራው ፡ አጠገብ ፡
በእርሱ ፡ ትይዩ ፡ እየሄደ ፡ ይራገም ÷ ድንጋ
ይም ፡ ይወረውር ÷ ትቢ.ያም ፡ ይበትን ፡ ነበር ።
፲፬ ንጉሡና ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበረው ፡ ሕዝብ ፡
ሁሉ ፡ ደክመው ፡ ነበር ÷ በዚ.ያም ፡ ዐረፉ ።

፲፭ አቤሴሎምና ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ የእስራኤልም ፡
ሰዎች ፡ አኪ.ጦፌልም ፡ ወደ ፡ ኢ.የሩሳሌም ፡
፲፮ መጡ ። የዳዊትም ፡ ወዳጅ ፡ አርካዊው ፡ ኩሲ ፡
ወደ ፡ አቤሴሎም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ኩሲ ፡— ሺህ ፡
፲፯ ዓመት ፡ ያንግሥህ ፡ አለው ። አቤሴሎምም ፡
ኩሲን ፡—ስለ ፡ ወዳጅህ ፡ ያደረግኸው ፡ ቸርነት ፡
ይህ ፡ ነውን ? ከወዳጅህ ፡ ጋር ፡ ያልሄድህ ፡ ስለ ፡
፲፰ ምንድር ፡ ነው ? አለው ። ኩሲም ፡ አቤሴሎ
ምን ፡—እንዲህ ፡ አይደለም ፤ ከእግዚአብሔር ፡
ከዚህም ፡ ሕዝብ ፡ ከእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
ለተመረጠው ፡ ለእርሱ ፡ እሆናለሁ ፡ ከእርሱም ፡
፲፱ ጋር ፡ እቀመጣለሁ ። ዳግምም ፡ የማገለግል ፡
ለማን ፡ ነው ? በንጉሥ ፡ ልጅ ፡ ፊት ፡ አይደለ
ምን ? በአባትህ ፡ ፊት ፡ እንዳገለገልሁ ፡ እን
ዲሁ ፡ በአንተ ፡ ፊት ፡ እሆናለሁ ፡ አለው ።

፳ አቤሴሎምም ፡ አኪ.ጦፌልን ፡— ምክሩ ÷
፳፩ ምን ፡ እናድርግ ? አለው ። አኪ.ጦፌል ም ፡

አቤሴሎምን ፡— ቤት ፡ ሊጠብቁ ፡ ወደ ፡ ተዋ
ቸው ፡ ወደ ፡ አባትህ ፡ ቁባቶች ፡ ግባ ፤ እስራኤ
ልም ፡ ሁሉ ፡ አባትህን ፡ እንዳሳፈርኸው ፡ ይሰ
ማሉ ፤ ከአንተም ፡ ጋር ፡ ያሉት ፡ ሁሉ ፡ እጃቸው ፡
፳፪ ይበረታል ፡ አለው ። ለአቤሴሎምም ፡ በሰገነት ፡
ላይ ፡ ድንኳን ፡ ተከሉለት ፤ አቤሴሎምም ፡ በእ
ስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ አባቱ ፡ ቁባቶች ፡
፳፫ ገባ ። በዚያም ፡ ወራት ፡ የመከራት ፡ የአኪጦ
ፌል ፡ ምክር ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ እንደ ፡
መጠየቅ ፡ ነበረች ፤ የአኪጦፌልም ፡ ምክር ፡
ሁሉ ፡ ከዳዊትና ፡ ከአቤሴሎም ፡ ጋር ፡ እንዲሁ ፡
ነበረች ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ አኪጦፌልም ፡ አቤሴሎምን ፡— አሥራ ፡
ሁለት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ልምረጥና ፡ በዚህች ፡
፪ ሌሊት ፡ ተነሥቼ ፡ ዳዊትን ፡ ላሳድድ ። ደክሞና ፡
እጁ ፡ ዝሎ ፡ ሳለ ፡ እወድቅበታለሁ ÷ አስፈራ
ውማለሁ ፤ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ ሕዝብ ፡
ሁሉ ፡ ይሸሻል ÷ ንጉሡንም ፡ ብቻውን ፡ እመ
፫ ታዋለሁ ፤ ሙሽራ ፡ ወደ ፡ ባልዋ ፡ እንደምትመ
ለስ ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እመልሰዋ
ለሁ ፤ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ደኅና ፡ ይሆናል ፤ የምት
፬ ፈልገው ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ብቻ ፡ ነው ። ነገሩም ፡
አቤሴሎምንና ፡ የእስራኤልን ፡ ሽማግሌዎች ፡
ሁሉ ፡ ደስ ፡ አሰኘ ።

፭ አቤሴሎምም ፡— አርካዊውን ፡ ኩሲን ፡ ጥሩ ÷
ደግሞም ፡ እርሱ ፡ የሚለውን ፡ እንስማ ፡ አለ ።
፮ ኩሲም ፡ ወደ ፡ አቤሴሎም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ አቤ
ሴሎም ፡— አኪጦፌል ፡ ያለው ፡ ይህ ፡ ነው ፤
ነገሩን ፡ እናድርገው ፡ ዘንድ ፡ ይገባልን ? ባይሆን ፡
፯ ግን ፡ አንተ ፡ ንገረን ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ። ኩሲም ፡
አቤሴሎምን ፡— አኪጦፌል ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡
የመከራት ፡ ምክር ፡ መልካም ፡ አይደለችም ፡
፰ አለው ። ኩሲ ፡ ደግሞ ፡ አለ ፡— ግልገሎችዋ ፡
በዱር ፡ በተነጠቁ ፡ ጊዜ ፡ ድብ ፡ መራራ ፡ እንደ ፡
ሆነች ፡ በልባቸው ፡ መራሮች ፡ እጅግም ፡ ኃያ
ላን ፡ መሆናቸውን ፡ አባትህንና ፡ ሰዎቹን ፡ ታው
ቃለህ ፤ አባትህ ፡ አርበኛ ፡ ነው ÷ ከሕዝብም ፡
፱ ጋር ፡ አያድርም ። አሁንም ፡ ምናልባት ፡ በአ
ንድ ፡ ጕድጓድ ፡ ወይም ፡ በማናቸውም ፡ ስፍራ ፡
ተሸሽጎ ፡ ይሆናል ፤ በመጀመሪያም ፡ ከእነርሱ ፡
አያሌዎች ፡ ቢወድቁ ÷ የሚሰማው ፡ ሁሉ ፡—
አቤሴሎምን ፡ የተከተለው ፡ ሕዝብ ፡ ተመታ ፡
፲ ይላል ። እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ አባትህ ፡ ኃያል ፡
እንደ ፡ ሆነ ÷ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ያሉት ፡
ሰዎች ፡ ጽኑዓን ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ያውቃልና ፡
ጽኑዕ ፡ ልቡም ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ልብ ፡ የሆነው ፡
፲፩ ፈጽሞ ፡ ይቀልጣል ። ነገር ፡ ግን ፡ የምመክርህ ፡
ይህ ፡ ነው ፤ ከዳን ፡ እስከ ፡ ቤርሳቤህ ፡ ያለ ፡ እስ
ራኤል ፡ ሁሉ ፡ በብዛቱ ፡ እንደ ፡ በሕር ፡ አሸዋ ፡
ሆኖ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ይሰብሰብ ÷ አንተም ፡ በመ
፲፪ ካከላቸው ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ ውጣ ። እርሱንም ፡
ወደምናገኝበት ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ ስፍራ ፡ እንደር
ስበታለን ÷ ጠልም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እንደሚ
ወድቅ ፡ እንወርድበታለን ፤ እርሱና ፡ ከእርሱም ፡
ጋር ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ አና
፲፫ ስቀርም ። ወደ ፡ ከተማም ፡ ቢገባ ፡ እስራኤል ፡
ሁሉ ፡ ወደዚያች ፡ ከተማ ፡ ገመድ ፡ ይወስዳል ÷
እኛም ፡ አንድ ፡ ድንጋይ ፡ እንኳ ፡ እስከማይገኝ
ባት ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ወንዙ ፡ ውስጥ ፡ እንስባታ
፲፬ ለን ። አቤሴሎምና ፡ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡
ሁሉ ፡— የአርካዊው ፡ የኩሲ ፡ ምክር ፡ ከአኪ
ጦፌል ፡ ምክር ፡ ይሻላል ፡ አሉ ። እግዚአብ
ሔርም ፡ በአቤሴሎም ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ያመጣ ፡
ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ መልካሚቱን ፡ የአኪጦ
ፌልን ፡ ምክር ፡ እንዲበትን ፡ አዘዘ ።

፲፭ ኩሲም ፡ ለካህናቱ ፡ ለሳዶቅና ፡ ለአብያታር ፡—
አኪጦፌል ፡ ለአቤሴሎምና ፡ ለእስራኤል ፡ ሽማ
ግሌዎች ፡ እንዲህና ፡ እንዲህ ፡ መክሮአል ፤ እኔ ፡
፲፮ ግን ፡ እንዲህና ፡ እንዲህ ፡ መክሬአለሁ ። አሁን ፡
እንግዲህ ፡ ንጉሡና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ያለው ፡
ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ እንዳይዋጡ ÷ ፈጥናችሁ ፡—
ሳትዘገዩ ፡ ተሻገር ፡ እንጂ ፡ በዚህች ፡ ሌሊት ፡
በምድረ ፡ በዳ ፡ መሻገሪያ ፡ አትደር ፡ ብላችሁ ፡
፲፯ ለዳዊት ፡ ንገሩት ፡ አላቸው ። ዮናታንና ፡ አኪ
ማአስ ፡ ተገልጠው ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ይገቡ ፡
ዘንድ ፡ አልቻሉም ፡ ነበርና ፡ በዓይንሮጌል ፡ ተቀ
ምጠው ፡ ነበር ፤ አንዲቱም ፡ ባሪያ ፡ ሄዳ ፡ ትነግ
ራቸው ፡ ነበር ፤ እነርሱም ፡ ሄደው ፡ ለንጉሡ ፡
፲፰ ለዳዊት ፡ ይነግሩት ፡ ነበር ። አንድ ፡ ብላቴናም ፡
አይቶ ፡ ለአቤሴሎም ፡ ነገረው ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡
ፈጥነው ፡ ሄዱ ፤ ወደ ፡ ብራቂምም ፡ ወደ ፡
አንድ ፡ ሰው ፡ ቤት ፡ መጡ ፤ በግቢውም ፡
ውስጥ ፡ ጕድጓድ ፡ ነበረ ÷ ወደዚያም ፡ ውስጥ ፡
፲፱ ወረዱ ። ሴቲቱም ፡ በጕድጓዱ ፡ አፍ ፡ ላይ ፡
ዳውጃ ፡ ዘረጋችበት ÷ የተከካ ፡ እህልም ፡ በላዩ ፡
፳ አሰጣችበት ፤ ነገሩም ፡ እንዲህ ፡ ተሰወረ ።
የአቤሴሎም ፡ ባሪያዎች ፡ ወደ ፡ ሴቲቱ ፡ ወደ ፡
ቤት ፡ መጥተው ፡— አኪማአስና ፡ ዮናታን ፡ የት ፡
አሉ ? አሉ ፤ ሴቲቱም ፡— ፈፋውን ፡ ተሻግረው ፡
ሄዱ ፡ አለቻቸው ። እነርሱም ፡ ፈልገው ፡ ባላገ
ኙአቸው ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ።

፳፩ ከሄዱም ፡ በኋላ ፡ እነርሱ ፡ ከጕድጓዱ ፡ ወጥ
ተው ፡ ሄዱ ÷ ለንጉሡም ፡ ለዳዊት ፡ ነገሩት ÷
ዳዊትንም ፡— አኪጦፌል ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ እን
ዲህ ፡ መክሮአልና ፡ ተነሡ ÷ ፈጥናችሁም ፡ ውኃ
፳፪ ውን ፡ ተሻገሩ ፡ አሉት ። ዳዊትና ፡ ከእርሱም ፡
ጋር ፡ የነበሩት ፡ ሁሉ ፡ ተነሥተው ፡ ዮርዳኖ
ስን ፡ ተሻገሩ ፤ እስኪነጋም ፡ ድረስ ፡ ዮርዳኖ
ስን ፡ ሳይሻገር ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ አል
ቀረም ።

፳፫ አኪጦፌልም ፡ ምክሩን ፡ እንዳልተከተሉ ፡
በየ ፡ ጊዜ ፡ አህያውን ፡ ጫነ ÷ ተነሥቶም ፡ ወደ ፡
ቤቱ ፡ ወደ ፡ ከተማው ፡ ሄደ ፤ ቤቱንም ፡ አደራ
ጅቶ ፡ በገዛ ፡ እጁ ፡ ታንቆ ፡ ሞተ ÷ በአባቱም ፡
መቃብር ፡ ተቀበረ ።

፳፬ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ መሃናይም ፡ መጣ ፤ አቤሴ

ሎምም ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡
፳፬ ሁሉ ፡ ዮርዳኖስን ፡ ተሻገሩ ። አቤሴሎምም ፡
በጭፍራው ፡ ላይ ፡ በኢዮአብ ፡ ስፍራ ፡ አሜሳ
ይን ፡ ሾመ ፤ አሜሳይም ፡ የይስማኤላዊ ፡ ሰው ፡
የዬቴር ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፤ እርሱም ፡ የኢዮአብን ፡
እናት ፡ የጽሩያን ፤ እኅት ፡ የናዖስን ፡ ልጅ ፡ አቢ
፳፭ ግያን ፡ አግብቶ ፡ ነበር ። እስራኤልና ፡ አቤሴ
ሎምም ፡ በገለዓድ ፡ ምድር ፡ ሰፈሩ ።
፳፮ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ መሃናይም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡
በአሞን ፡ ልጆች ፡ አገር ፡ በረባት ፡ የነበረ ፡ የና
ዖስ ፡ ልጅ ፡ ሱኤስቢ ፥ የሎዶባርም ፡ ሰው ፡ የዓ
ሚኤል ፡ ልጅ ፡ ማኪር ፥ የሮግሊምም ፡ ሰው ፡
፳፯፡፳፰ ገለዓዳዊው ፡ ቤርዜሊ ፡— ሕዝቡ ፡ በምድረ ፡
በዳ ፡ ተርቦአል ፥ ደክሞአል ፥ ተጠምቶአል ፡
ብለው ፥ ምንጣፍ ፥ ዳካ ፥ የሸክላም ፡ ዕቃ ፥ ይበ
ሉም ፡ ዘንድ ፡ ስንዴ ፥ ገብስ ፥ ዱቄት ፥ የተጠበሰ ፡
እሸት ፥ ባቄላ ፥ ምስር ፥ የተቈላ ፡ሽንብራ ፥ ማር ፥
ቅቤ ፥ በጎች ፥ የላምም ፡ እርጎ ፡ ለዳዊትና ፡ ከእ
ርሱ ፡ ጋር ፡ ለነበሩት ፡ ሕዝብ ፡ አመጡላቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ ዳዊትም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩትን ፡ ሕዝብ ፡
ቈጠረ ፥ ሻለቆችንና ፡ የመቶ ፡ አለቆችንም ፡
፪ ሾመላቸው ። ዳዊትም ፡ ሕዝቡን ፡ ከኢዮአብ ፡
እጅ ፡ በታች ፡ ሢሶውን ፥ ከኢዮአብም ፡ ወን
ድም ፡ ከጽሩያ ፡ ልጅ ፡ ከአቢሳ ፡ እጅ ፡ በታች ፡
ሢሶውን ፥ ከጌት ፡ ሰውም ፡ ከኢታይ ፡ እጅ ፡
በታች ፡ ሢሶውን ፡ ሰደደ ። ንጉሡም ፡ ሕዝ
ቡን ፡— እኔ ፡ ደግሞ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እወጣ
፫ ለሁ ፡ አላቸው ። ሕዝቡ ፡ ግን ፡— አትወጣም ፤
ብንሸሽ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ አያስቡም ፤ ከእኛም ፡ እኩ
ሌታው ፡ ቢሞት ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ አያስቡም ፤ አንተ ፡
ግን ፡ ለብቻህ ፡ ከእኛ ፡ ከአሥሩ ፡ ሺህ ፡ ይልቅ ፡
ትበልጣለህ ፤ አሁንም ፡ በከተማ ፡ ተቀምጠህ ፡
፬ ብትረዳን ፡ ይሻላል ፡ አሉ ። ንጉሡም ፡— መል
ካም ፡ የሚመስላችሁን ፡ አደርጋለሁ ፡ አላቸው ።
ንጉሡም ፡ በበሩ ፡ አጠገብ ፡ ቆመ ፥ ሕዝቡም ፡
ሁሉ ፡ መቶ ፡ በመቶ ፡ ሺህ ፡ በሺህ ፡ እየሆኑ ፡
፭ ወጡ ። ንጉሡም ፡ ኢዮአብንና ፡ አቢሳን ፡ ኢታ
ይንም ፡— ለብላቴናው ፡ ለአቤሴሎም ፡ ስለ ፡ እኔ ፡
ራሩለት ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ። ንጉሡም ፡ ስለ ፡
አቤሴሎም ፡ አለቆቹን ፡ ሁሉ ፡ ሲያዝዝ ፡ ሕዝቡ ፡
ሁሉ ፡ ሰማ ።
፮ ሕዝቡም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡
መጣ ፤ ሰልፉም ፡ በኤፍሬም ፡ ዱር ፡ ውስጥ ፡ ሆነ ።
፯ በዚያም ፡ የእስራኤል ፡ ሕዝብ ፡ በዳዊት ፡ ባሪ
ያዎች ፡ ፊት ፡ ተመቱ ፥ በዚያም ፡ ቀን ፡ ታላቅ ፡
ውጊያ ፡ በዚያ ፡ ሆነ ፥ ሀያ ፡ ሺህ ፡ ሰውም ፡ ሞተ ።
፰ ከዚያም ፡ ሰልፉ ፡ በአገሩ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ላይ ፡
ተበተነ ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሰይፍ ፡ ከዋጠው ፡
ሕዝብ ፡ ይልቅ ፡ ዱር ፡ ብዙ ፡ ዋጠ ።
፱ አቤሴሎም ፡ ከዳዊት ፡ ባሪያዎች ፡ ጋር ፡ በድ
ንገት ፡ ተገናኘ ፤ አቤሴሎምም ፡ በበቅሎ ፡ ተቀ
ምጦ ፡ ነበር ፥ በቅሎውም ፡ ብዙ ፡ ቅርንጫፍ ፡
ባለው ፡ በታላቅ ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ ገባ ፥ ራሱም ፡
በዛፉ ፡ ተያዘ ፤ በሰማይና ፡ በምድር ፡ መካከል ፡
ተንጠለጠለ ፥ ተቀምጦበትም ፡ የነበረ ፡ በቅሎ ፡
፲ አለፈ ። አንድ ፡ ሰውም ፡ አይቶ ፡— እነሆ ፥
አቤሴሎም ፡ በትልቅ ፡ ዛፍ ፡ ላይ ፡ ተንጠ
ልጥሎ ፡ አየሁ ፡ ብሎ ፡ ለኢዮአብ ፡ ነገረው ።
፲፩ ኢዮአብም ፡ ለነገረው ፡ ሰው ፡— እነሆ ፥ ካየ
ኸው ፡ ለምን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ አልመታኸውም ?
አሥር ፡ ብርና ፡ አንድ ፡ ድግ ፡ እሰጥህ ፡ ነበር ፡
፲፪ አለው ። ሰውዮውም ፡ ኢዮአብን ፡— እኛ ፡ ስን
ሰማ ፡ ንጉሡ ፡ አንተንና ፡ አቢሳን ፡ ኢታይ
ንም ፡— ብላቴናውን ፡ አቤሴሎምን ፡ ማንም ፡
እንዳይነካው ፡ ተጠንቀቁ ፡ ብሎ ፡ አዝዞአልና ፡
ሺህ ፡ ብር ፡ በእጄ ፡ ላይ ፡ ብትመዝን ፡ እጄን ፡
በንጉሡ ፡ ልጅ ፡ ላይ ፡ ባልዘረጋሁም ፡ ነበር ።
፲፫ እኔ ፡ ቅሉ ፡ በነፍሱ ፡ ላይ ፡ ብወነጅል ፡ ኖሮ ፡
ይህ ፡ ከንጉሥ ፡ ባልተሰወረም ፥ አንተም ፡ በተ
፲፬ ነሣህብኝ ፡ ነበር ፡ አለው ። ኢዮአብም ፡— እኔ ፡
ከአንተ ፡ ጋር ፡ እንዲህ ፡ እዘገይ ፡ ዘንድ ፡ አልች
ልም ፡ ብሎ ፡ ሦስት ፡ ጦሮች ፡ በእጁ ፡ ወሰደ ፥
አቤሴሎምም ፡ገና ፡ በዛፍ ፡ ላይ ፡ ተንጠልጥሎ ፡
፲፭ ሕያው ፡ ሳለ ፡ በልቡ ፡ ላይ ፡ ተከላቸው ። አሥ
ሩም ፡ የኢዮአብ ፡ ጋሻ ፡ጃግሬዎች ፡ ከበቡት ፥
አቤሴሎምንም ፡ መትተው ፡ ገደሉት ።
፲፮ ኢዮአብም ፡ ሕዝቡን ፡ ከልክሎ ፡ ነበርና ፡
ቀንደ ፡ መለከት ፡ ነፋ ፥ ሕዝቡም ፡ እስራኤልን ፡
፲፯ ከማሳደድ ፡ ተመለሰ ። አቤሴሎምንም ፡ ወስ
ደው ፡ በዱር ፡ ባለ ፡ በታላቅ ፡ ጕድጓድ ፡ ውስጥ ፡
ጣሉት ፥ እጅግም ፡ ታላቅ ፡ የሆነ ፡ የድንጋይ ፡
ክምር ፡ ከመሩበት ፤ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ እያን
፲፰ ዳንዱ ፡ ወደ ፡ ድንኳኑ ፡ ሸሸ ። አቤሴሎምም ፡
ሕያው ፡ ሳለ ፡— ለስሜ ፡ መታሰቢያ ፡ የሚሆን ፡
ልጅ ፡ የለኝም ፡ ብሎ ፡ ሐውልት ፡ ወስዶ ፡ በን
ጉሥ ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ ለራሱ ፡ አቁሞ ፡ ነበር ፤
ሐውልቱንም ፡ በስሙ ፡ ጠርቶት ፡ ነበር ፤ እስከ ፡
ዛሬም ፡ ድረስ ፡ የአቤሴሎም ፡ መታሰቢያ ፡
ተብሎ ፡ ይጠራል ።
፲፱ የሳዶቅ ፡ ልጅ ፡ አኪማአስ ፡ ግን ፡— እግዚአ
ብሔር ፡ ጠላቶቹን ፡ እንደ ፡ ተበቀለለት ፡ሮጬ ፡
፳ ለንጉሥ ፡ የምስራች ፡ ልንገር ፡ አለ ። ኢዮአ
ብም ፡— በሌላ ፡ ቀን ፡ እንጂ ፡ ዛሬ ፡ ወሬ ፡ አት
ናገርም ፤ የንጉሥ ፡ ልጅ ፡ ሞቶአልና ፡ ዛሬ ፡
፳፩ ወሬ ፡ አትናገርም ፡ አለው ። ኢዮአብም ፡
ኵሲን ፡— ሂድ ፡ ያየኸውንም ፡ ለንጉሡ ፡ ንገር ፡
አለው ። ኵሲም ፡ ለኢዮአብ ፡ እጅ ፡ ነሥቶ ፡
፳፪ ሮጠ ። ዳግመኛም ፡ የሳዶቅ ፡ ልጅ ፡ አኪማአስ ፡
ኢዮአብን ፡— የሆነ ፡ ሆኖ ፡ ኵሲን ፡ ተከትዬ ፥
እበክህ ፥ ልሩጥ ፡ አለው ። ኢዮአብም ፡— ልጄ ፡
ሆይ ፥ መልካም ፡ ወሬ ፡ የምትወስድ ፡ አይደለ
ህምና ፡ ትሮጥ ፡ ዘንድ ፡ ለምን ፡ ትወድዳለህ ?
፳፫ አለ ። እርሱም ፡— እኔ ፡ ብሮጥ ፡ ምን ፡ ይገድ
ዳል ? አለ ። እርሱም ፡— ሩጥ ፡ አለው ። አኪማ
አስም ፡ በሜዳው ፡ መንገድ ፡ በኩል ፡ ሮጠ ፥
ኵሲንም ፡ ቀደመው ።

፳፬ ዳዊትም ፡ በሁለት ፡ በር ፡ መካከል ፡ ተቀምጦ ፡
ነበር ፤ ዘበኛውም ፡ በቅጥሩ ፡ ላይ ፡ ወዳለው ፡
ወደ ፡ በሩ ፡ ሰገነት ፡ ወጣ ፥ ዓይኑንም ፡ አቅንቶ ፡
፳፭ ብቻውን ፡ የሚሮጥ ፡ ሰው ፡ አየ ። ዘበኛውም ፡
ለንጉሡ ፡ ሊነግረው ፡ ጮኸ ። ንጉሡም ፡— ብቻ
ውን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በአፉ ፡ ወሬ ፡ ይኖራል ፡
፳፮ አለ ። እርሱም ፡ ፈጥኖ ፡ ቀረበ ። ዘበኛውም ፡
ሌላ ፡ ሰው ፡ ሲሮጥ ፡ አየ ፤ ዘበኛውም ፡ ለደጅ ፡
ጠባቂው ፡ ጮኸ ፡— እነሆ ፥ ብቻውን ፡ የሚሮጥ ፡
ሌላ ፡ ሰው ፡ አየሁ ፡ አለ ። ንጉሡም ፡— እርሱ ፡
፳፯ ደግሞ ፡ ወሬ ፡ ይዞ ፡ ይሆናል ፡ አለ ። ዘበኛ
ውም ፡— የፊተኛው ፡ ሩጫ ፡ እንደ ፡ ሳዶቅ ፡
ልጅ ፡ እንደ ፡ አኪማአስ ፡ ሩጫ ፡ ይመስላል ፡
አለ ፤ ንጉሡም ፡— እርሱ ፡ መልካም ፡ ሰው ፡
ነው ፥ መልካምም ፡ ወሬ ፡ ያመጣል ፡ አለ ።

፳፰ አኪማአስም ፡ ጮኸ ፡ ንጉሡን ፡— ሁሉ ፡
ደኅና ፡ ሆኖአል ፡ አለው ። በንጉሡም ፡ ፊት ፡
በምድር ፡ ላይ ፡ በግምባሩ ፡ ተደፍቶ ፡— በን
ጉሡ ፡ በጌታዬ ፡ ላይ ፡ እጃቸውን ፡ ያነሡትን ፡
ሰዎች ፡ አሳልፎ ፡ የሰጠ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብ
፳፱ ሔር ፡ ይመስገን ፡ አለ ። ንጉሡም ፡— ብላቴ
ናው ፡ አቤሴሎም ፡ ደኅና ፡ ነውን ? አለ ። አኪ
ማአስም ፡— ኢዮአብ ፡ እኔን ፡ ባሪያህንና ፡ የን
ጉሡን ፡ ባሪያ ፡ በላከ ፡ ጊዜ ፡ ትልቅ ፡ ሽብር ፡
አይቻለሁ ፥ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ አላወቅ
፴ ሁም ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ። ንጉሡም ፡— ፈቀቅ ፡
ብለህ ፡ ቁም ፡ አለ ፤ እርሱም ፡ ፈቀቅ ፡ ብሎ ፡
ቆመ ።

፴፩ እነሆም ፥ ኵሲ ፡ መጣ ፤ ኵሲም ፡— እግዚአ
ብሔር ፡ በላይህ ፡ የተነሡትን ፡ ሁሉ ፡ ዛሬ ፡
እንደ ፡ ተበቀለልህ ፡ ለጌታዬ ፡ ለንጉሡ ፡ ወሬ ፡
፴፪ አምጥቻለሁ ፡ አለ ። ንጉሡም ፡ ኵሲን ፡— ብላ
ቴናው ፡ አቤሴሎም ፡ ደኅና ፡ ነውን ? አለው ።
ኵሲም ፡— የጌታዬ ፡ የንጉሡ ፡ ጠላቶች ፥ በክ
ፉም ፡ የተነሡብህ ፡ ሁሉ ፡ እንደዚያ ፡ ብላቴና ፡
፴፫ ይሁኑ ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ። ንጉሡም ፡ እጅግ ፡
አዘነ ፥ በበሩም ፡ ላይ ፡ ወዳለችው ፡ ቤት ፡ ወጥቶ ፡
አለቀሰ ፤ ሲሄድም ፡— ልጄ ፡ አቤሴሎም ፡ ሆይ ፥
ልጄ ፥ ልጄ ፡ አቤሴሎም ፡ ሆይ ፥ በአንተ ፡ ፋንታ ፡
ሞቼ ፡ ኖሮ ፡ ቢሆን ፥ ልጄ ፡ አቤሴሎም ፥ ልጄ ፡
ሆይ ፡ ይል ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ ኢዮአብም ፡ ንጉሡ ፡ ስለ ፡ አቤሴሎም ፡ እን
፪ ዳለቀሰና ፡ ዋይ ፡ ዋይ ፡ እንዳለ ፡ ሰማ ። በዚ
ያም ፡ ቀን ፡— ንጉሡ ፡ ስለ ፡ ልጁ ፡ አዘነ ፡ ሲባል ፡
ሕዝቡ ፡ ሰምቶአልና ፡ የዚያ ፡ ቀን ፡ ድል ፡ በሕ
ዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኀዘን ፡ ተለወጠ ።
፫ ሕዝቡም ፡ ከሰልፍ ፡ የሸሸ ፡ ሕዝብ ፡ አፍሮ ፡ ወደ ፡
ኋላው ፡ እንዲል ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡
፬ ተሰርቆ ፡ ገባ ። ንጉሡም ፡ ፊቱን ፡ ሸፈነ ፥ ንጉ
ሡም ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡— ልጄ ፡ አቤሴሎም ፡
ሆይ ፥ ልጄ ፡ አቤሴሎም ፥ ልጄ ፡ ሆይ ፡ እያለ ፡
፭ ይጮኽ ፡ ነበር ። ኢዮአብም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡
ወደ ፡ ቤት ፡ ገብቶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ዛሬ ፡ ነፍ
ስህንና ፡ የወንዶችና ፡ የሴቶች ፡ ልጆችህን ፡
ነፍስ ፡ የሚስቶችህንና ፡ የቁባቶችህን ፡ ነፍስ ፡
ያዳኑትን ፡ የባሪያዎችህን ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ዛሬ ፡
፮ አሳፍረሃል ፤ አንተ ፡ የሚጠሉህን ፡ ትወድዳ
ለህ ፥ የሚወድዱህንም ፡ ትጠላለህ ። መሳፍን
ትህንና ፡ ባሪያዎችህን ፡ እንዳታስብ ፡ ዛሬ ፡ ገል
ጠሃል ፤ ዛሬ ፡ ሁላችን ፡ ሞተን ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡
አቤሴሎምም ፡ ድኖ ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ ደስ ፡ ያሰ
፯ ኝህ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ዛሬ ፡ አያለሁ ። አሁን ፡
እንግዲህ ፡ ተነሥተህ ፡ ውጣ ፥ ለባሪያዎች
ህም ፡ የሚያጽናናቸውን ፡ ነገር ፡ ተናገራቸው ፤
ያልወጣህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ሰው ፡
ከአንተ ፡ ጋር ፡ በዚህች ፡ ሌሊት ፡ እንዳይቀር ፡
በእግዚአብሔር ፡ እምላለሁ ፤ ይህም ፡ ከብላ
ቴናነትህ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ካገ
ኘህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ታላቅ ፡
፰ መከራ ፡ ይሆንብሃል ። ንጉሡም ፡ ተነሥቶ ፡
በበሩ ፡ ተቀመጠ ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ንጉሡ ፡
በበሩ ፡ እንደ ፡ ተቀመጠ ፡ ሰማ ፤ ሕዝቡም ፡
ሁሉ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ፊት ፡ መጣ ።

እስራኤልም ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ድንኳኑ ፡
፱ ሸሽቶ ፡ ነበር ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በእስራኤል ፡
ነገድ ፡ ሁሉ ፡ ውስጥ ፡— ንጉሡ ፡ ከጠላቶቻችን ፡
እጅ ፡ ታድጎናል ፥ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ እጅ ፡
አድኖናል ፤ አሁንም ፡ ስለ ፡ አቤሴሎም ፡ ከአ
፲ ገር ፡ ሸሽቶአል ። በላያችን ፡ እንዲሆን ፡ የቀባ
ነው ፡ አቤሴሎም ፡ በሰልፍ ፡ ሞቶአል ፤ አሁ
ንም ፡ እንግዲህ ፡ ንጉሡን ፡ ለመመለስ ፡ ስለ ፡
ምን ፡ ዝም ፡ ትላላችሁ ? እያለ ፡ እርስ ፡ በርሱ ፡
ይከራከር ፡ ነበር ።

፲፩ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ለካህናቱ ፡ ለሳዶቅና ፡
ለአብያታር ፡ ልኮ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— ለይ
ሁዳ ፡ ሽማግሌዎች ፡ እንዲህ ፡ ብላችሁ ፡ ተናገ
ሩአቸው ፡— የእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ነገር ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ ደርሶአልና ፡ ንጉሡን ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡
፲፪ ከመመለስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ዘገያችሁ ? እናንተ ፡
ወንድሞቼ ፥ የአጥንቴ ፡ ፍላጭና ፡ የሥጋዬ ፡
ቊራጭ ፡ ናችሁ ፤ እናንተ ፡ ንጉሡን ፡ ከመመ
፲፫ ለስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ዘገያችሁ ? ለአሜሳይም ፡—
አንተ ፡ የአጥንቴ ፡ ፍላጭና ፡ የሥጋዬ ፡ ቊራጭ ፡
አይደለህምን ? በዘመንህም ፡ ሁሉ ፡ በኢዮአብ ፡
ፋንታ ፡ በፊቴ ፡ የሠራዊት ፡ አለቃ ፡ ሳትሆን ፡
ብትቀር ፡ እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ያድርግብኝ ፡
፲፬ ይህንም ፡ ይጨምርብኝ ፡ በሉት ። የይሁዳንም ፡
ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ልብ ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ልብ ፡
አድርጎ ፡ አዘነበለ ፤ ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ልከው ፡—
አንተ ፡ ከባሪያዎችህ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ተመለስ ፡
አሉት ።

፲፭ ንጉሡም ፡ ተመልሶ ፡ እስከ ፡ ዮርዳኖስ ፡
ድረስ ፡ መጣ ። የይሁዳ ፡ ሰዎች ፡ ንጉሡን ፡
ሊቀበሉ ፡ ንጉሡንም ፡ ዮርዳኖስን ፡ ሊያሻግሩ ፡
፲፮ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ መጡ ። ከብራቂምም ፡ አገር ፡
የነበረው ፡ ብንያማዊው ፡ የጌራ ፡ ልጅ ፡ ሳሚ ፡

ከይሁዳ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ዳዊትን ፡ ሊቀበል ፡
፲፯ ፈጥኖ ፡ ወረደ ። ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ብንያማው
ያን ፡ የሆኑ ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፥ የሳኦልም ፡
ቤት ፡ ባሪያ ፡ ሲባ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ አሥራ ፡
አምስቱ ፡ ልጆችና ፡ ሀያው ፡ ባሪያዎች ፡ ነበሩ ፤
በንጉሡም ፡ ፊት ፡ ፈጥነው ፡ ዮርዳኖስን ፡ ተሻ
፲፰ ገሩ ። ታንኳውም ፡ የንጉሥን ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፡
ያሻግር ፡ ዘንድ ፡ ንጉሡም ፡ ደስ ፡ ያሰኘውን ፡
ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ይሻገር ፡ ነበር ። ንጉሡም ፡
ዮርዳኖስን ፡ ከተሻገረ ፡ በኋላ ፡ የጌራ ፡ ልጅ ፡
፲፱ ሳሚ ፡ በፊቱ ፡ ተደፋ ። ንጉሡንም ፡— ጌታዬ ፡
ሆይ ፥ ኃጢአቴን ፡ አትቍጠርብኝ ፤ ጌታዬ ፡
ንጉሡ ፥ ከኢየሩሳሌም ፡ በወጣህ ፡ ቀን ፡ ባሪ
ያህ ፡ የበደልሁህን ፡ አታስብብኝ ፥ ንጉሡም ፡
፳ በልቡ ፡ አያኑረው ። ባሪያህ ፡ በደለኛ ፡ እንደ ፡
ሆንሁ ፡ አውቄአለሁና ፡ እነሆ ፥ ከዮሴፍ ፡ ቤት ፡
ሁሉ ፡ አስቀድሜ ፡ ዛሬ ፡ መጣሁ ፥ ጌታዬንም ፡
፳፩ ንጉሡን ፡ ልቀበል ፡ ወረድሁ ፡ አለው ። የጽ
ሩያ ፡ ልጅ ፡ አቢሳ ፡ ግን ፡— ሳሚ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ የቀባውን ፡ ሰድቦአልና ፡ ሞት ፡ የተገባው ፡
፳፪ አይደለምን ? አለ ። ዳዊትም ፡— እናንተ ፡ የጽ
ሩያ ፡ ልጆች ፥ እኔ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አለኝ ?
ዛሬ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ጠላቶች ፡ ትሆኑብኛላችሁ ?
ዛሬስ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ሰው ፡ ሊሞት ፡ ይገ
ባልን ? ዛሬስ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ነገሥሁ ፡
፳፫ አላወቅሁምን ? አለ ። ንጉሡም ፡ ሳሚን ፡—
አትሞትም ፡ አለው ። ንጉሡም ፡ ማለለት ።
፳፬ የሳኦልም ፡ ልጅ ፡ ሜምፊቦስቴ ፡ ንጉሡን ፡
ሊቀበል ፡ ወረደ ፤ ንጉሡም ፡ ከሄደ ፡ ጀምሮ ፡
በደኅና ፡ እስከ ፡ ተመለሰበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡
እግሩን ፡ አልጠገነም ፥ ጢሙንም ፡ አልቈረ
፳፭ ጠም ፥ ልብሱንም ፡ አላጠበም ፡ ነበር ። ንጉሡ
ንም ፡ ሊቀበለው ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡
ንጉሡ ፡— ሜምፊቦስቴ ፡ ሆይ ፥ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ስለ ፡
፳፮ ምን ፡ አልወጣህም ? አለው ። እርሱም ፡ መልሶ ፡
አለ ፡— ጌታዬ ፥ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ ባሪያዬ ፡ አታለ
ለኝ ፤ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ አንካሳ ፡ ነኝና ፡— ከንጉሥ ፡
ጋር ፡ እሄድ ፡ ዘንድ ፡ የምቀመጥበትን ፡ አህያ ፡
፳፯ ልጫን ፡ አልሁት ። እርሱም ፡ እኔን ፡ ባሪያህን ፡
ለጌታዬ ፡ ለንጉሡ ፡ አማ ፤ አንተ ፡ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡
ግን ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ ነህ ፤
፳፰ ደስም ፡ ያሰኘህን ፡ አድርግ ። የአባቴ ፡ ቤት ፡
ሁሉ ፡ በጌታዬ ፡ በንጉሡ ፡ ዘንድ ፡ ሞት ፡ የሚ
ገባቸው ፡ ነበሩ ፤ አንተ ፡ ግን ፡ እኔን ፡ ባሪያህን ፡
በገበታህ ፡ በሚበሉ ፡ መካከል ፡ አስቀመጥኸኝ ፤
ለንጉሥ ፡ ደግሞ ፡ ለመናገር ፡ ምን ፡ መብት ፡
፳፱ አለኝ ? ንጉሡም ፡— ነገርህን ፡ ለምን ፡ ታበዛ
ለህ ? አንተና ፡ ሲባ ፡ እርሻውን ፡ ትካፈሉ ፡
፴ ዘንድ ፡ ብያለሁ ፡ አለው ። ሜምፊቦስቴም ፡
ንጉሡን ፡— ጌታዬ ፡ ንጉሡ ፡ በደኅና ፡ ወደ ፡
ቤቱ ፡ ከተመለሰ ፡ እርሱ ፡ ሁሉን ፡ ይውሰደው ፡
አለው ።

፴፩ ገለዓዳዊውም ፡ ቤርዜሊ ፡ ከሮግሊም ፡ ወረደ ፤
ሊሸኘውም ፡ ከንጉሡ ፡ ጋር ፡ ዮርዳኖስን ፡ ተሻ
፴፪ ገረ ። ቤርዜሊም ፡ እጅግ ፡ ያረጀ ፡ የሰማንያ ፡
ዓመት ፡ ሽማግሌ ፡ ነበረ ፤ እጅግም ፡ ትልቅ ፡
ሰው ፡ ነበረና ፡ ንጉሡ ፡ በመሃናይም ፡ ሳለ ፡ ይቀ
፴፫ ልበው ፡ ነበር ። ንጉሡም ፡ ቤርዜሊን ፡— በኢየ
ሩሳሌም ፡ እቀልብህ ፡ ዘንድ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ እለፍ ፡
፴፬ አለው ። ቤርዜሊም ፡ ንጉሡን ፡ አለው ፡— ከን
ጉሡ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እወጣ ፡ ዘንድ ፡
፴፭ ከሕይወቴ ፡ ዘመን ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ቀረኝ ? ዛሬ ፡
የሰማንያ ፡ ዓመት ፡ ሽማግሌ ፡ ነኝ ፤ መልካሙ
ንና ፡ ክፉውን ፡ መለየት ፡ እችላለሁን ? እኔ ፡
ባሪያህ ፡ የምበላውንና ፡ የምጠጣውን ፡ ጣዕ
ሙን ፡ መለየት ፡ እችላለሁን ? የወንዱንና ፡ የሴቲ
ቱን ፡ ዘፈን ፡ ድምፅ ፡ መስማት ፡ እችላለሁን ? እኔ ፡
ባሪያህ ፡ በጌታዬ ፡ በንጉሡ ፡ ላይ ፡ ለምን ፡ እከ
፴፮ ብድብሃለሁ ? እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ዮርዳኖስን ፡ ተሻ
ግሬ ፡ ከንጉሡ ፡ ጋር ፡ ጥቂት ፡ ልሄድ ፡ ነበር ፤
ንጉሡ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ወረታ ፡ ለምን ፡ ይመል
፴፯ ስልኛል ? እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ተመልሼ ፡ በከተማዬ ፡
በአባቴና ፡ በእናቴ ፡ መቃብር ፡ አጠገብ ፥ እባ
ክህ ፥ ልሙት ። ነገር ፡ ግን ፡ ባሪያህን ፡ ከመዓ
ምን ፡ እይ ፤ እርሱ ፡ ከጌታዬ ፡ ከንጉሡ ፡ ጋር ፡
ይለፍ ፥ ደስ ፡ የሚያሰኝህንም ፡ ለእርሱ ፡ አድ
፴፰ ርግ ። ንጉሡም ፡— ከመዓም ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡
ይለፍ ፥ ደስ ፡ የሚያሰኝህንም ፡ አደርግለታለሁ ፤
አንተም ፡ ከእኔ ፡ የምትሻውን ፡ ሁሉ ፡ አደርግ
፴፱ ልሃለሁ ፡ አለው ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ዮርዳኖስን ፡
ተሻገረ ፥ ንጉሡም ፡ ተሻገረ ፤ ንጉሡም ፡ ቤር
ዜሊን ፡ ሳመው ፥ መረቀውም ፤ ወደ ፡ ስፍራ
ውም ፡ ተመለሰ ።

፵ ንጉሡም ፡ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ ተሻገረ ፥ ከመዓ
ምም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሄደ ፤ የይሁዳም ፡ ሕዝብ ፡
ሁሉ ፡ ደግሞም ፡ የእስራኤል ፡ ሕዝብ ፡ እኩ
፵፩ ሌታ ፡ ንጉሡን ፡ አሻገረው ። እነሆም ፥ የእስራ
ኤል ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡ መጡ ፥
ንጉሡንም ፡— ወንድሞቻችን ፡ የይሁዳ ፡ ሰዎች ፡
ለምን ፡ ሰረቁህ ? ንጉሡንም ፡ ቤተ ፡ ሰቡንም ፡
ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የዳዊትን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ዮር
፵፪ ዳኖስን ፡ አሻገሩ ? አሉት ። የይሁዳም ፡ ሰዎች ፡
ሁሉ ፡ ለእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ መልሰው ፡— ንጉሡ ፡
ለእኛ ፡ ቅርባችን ፡ ነው ፤ ስለ ፡ ምን ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡
ትቈጣላችሁ ? በውኑ ፡ ከንጉሡ ፡ አንዳች ፡ በል
ተናልን ? ወይስ ፡ እርሱ ፡ በረከት ፡ ሰጥቶናልን ?
፵፫ አሉ ። የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ለይሁዳ ፡ ሰዎች ፡
መልሰው ፡— በንጉሡ ፡ ዘንድ ፡ ለእኛ ፡ አሥር ፡
ክፍል ፡ አለን ፥ በዳዊትም ፡ ዘንድ ፡ ደግሞ ፡
ከእናንተ ፡ ይልቅ ፡ መብት ፡ አለን ፤ ስለ ፡ ምን ፡
ናቃችሁን ? ስለ ፡ ምንስ ፡ ንጉሣችንን ፡ ለመመ
ለስ ፡ ቀድሞ ፡ ምክር ፡ አልጠየቃችሁንም ? አሉ ።
የይሁዳም ፡ ሰዎች ፡ ቃል ፡ ከእስራኤል ፡ ሰዎች ፡
ቃል ፡ ይልቅ ፡ ጠነከረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ፡፡

፩፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ አንድ ፡ ብንያማዊ ፡ የቢክሪ ፡
ልጅ ፡ ስሙ ፡ ሳቤዔ ፡ የሚባል ፡ ምናምንቴ ፡ ሰው ፡
ነበረ ፤ እርሱም ፦ ከዳዊት ፡ ዘንድ ፡ እድል ፡
ፈንታ ፡ የለንም ፥ ከእሴይም ፡ ልጅ ፡ ዘንድ ፡
ርስት ፡ የለንም ፤ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ እያንዳን
ድህ ፡ ወደ ፡ ድንኳንህ ፡ ተመለስ ፡ ብሎ ፡ ቀንደ ፡
፪፤ መለከት ፡ ነፋ ፡፡ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
ከዳዊት ፡ ተለይተው ፡ የቢክሪን ፡ ልጅ ፡ ሳቤ
ዔን ፡ ተከተሉ ፤ የይሁዳ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ከዮር
ዳኖስ ፡ጀምረው ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እስኪደርሱ ፡
ንጉሣቸውን ፡ ተከተሉ ፡፡
፫፤ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡
መጣ ፤ ንጉሡም ፡ ቤቱን ፡ ሊጠብቁ ፡ የተዋቸ
ውን ፡ አሥሩን ፡ ቁባቶች ፡ ወስዶ ፡ ለጠባቂ ፡
ሰጣቸው ፥ ቀለብም ፡ ሰጣቸው ፥ ነገር ፡ ግን ፡
ወደ ፡ እነርሱ ፡ አልገባም ፤ በቤት ፡ ተዘግተው ፡
እስኪሞቱም ፡ ድረስ ፡ ባልቴቶች ፡ ሆነው ፡ ተቀ
መጡ ፡፡
፬፤ ንጉሡም ፡ አሜሳይን ፦ የይሁዳን ፡ ሰዎች ፡
ሁሉ ፡ በሦስት ፡ ቀን ፡ ውስጥ ፡ ጥራልኝ ፥ አን
፭፤ ተም ፡ አብረህ ፡ በዚህ ፡ ሁን ፡ አለው ፡፡ አሜሳ
ይም ፡ የይሁዳን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይጠራ ፡ ዘንድ ፡
ሄደ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ የተቀጠረውን ፡ ቀን ፡
፮፤ አሳልፎ ፡ ዘገየ ፡፡ ዳዊትም ፡ አቢሳን ፦ አሁን ፡
ከአቤሴሎም ፡ ይልቅ ፡ የሚጐዳን ፡ የቢክሪ ፡
ልጅ ፡ ሳቤዔ ፡ ነው ፤ እርሱ ፡ የተመሸጉትን ፡
ከተሞች ፡ አግኝቶ ፡ ከዓይናችን ፡ እንዳያመ
ልጥ ፥ አንተ ፡ የጌታህን ፡ ባሪያዎች ፡ ወስደህ ፡
፯፤ አሳድደው ፡ አለው ፡፡ አቢሳንም ፡ ተከትለው ፡
የኢዮአብ ፡ ሰዎች ፡ ከሊታውያንም ፡ ፈሊታው
ያንም ፡ ኃያላንም ፡ ሁሉ ፡ ሄዱ ፤ የቢክሪንም ፡
ልጅ ፡ ሳቤዔን ፡ ለማሳደድ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡
፰፤ ወጡ ፡፡ በገባዖንም ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ ታላቁ ፡
ድንጋይ ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ አሜሳይ ፡ ሊገናኛ
ቸው ፡ መጣ ፤ ኢዮአብም ፡ የሰልፍ ፡ ልብስ ፡
ለብሶ ፡ ነበር ፥ በላዩም ፡ መታጠቂያ ፡ ነበረ ፥
በወገቡም ፡ ላይ ፡ ሰገባ ፡ ያለው ፡ ሰይፍ ፡ ታጥቆ ፡
ነበር ፤ እርሱም ፡ ሲራመድ ፡ ሰይፉ ፡ ወደቀ ፡፡
፱፤ ኢዮአብም ፡ አሜሳይን ፦ ወንድሜ ፡ ሆይ ፥
ደኅና ፡ ነህን ? አለው ፡ ኢዮአብም ፡ አሜሳይን ፡
የሚስም ፡ መስሎ ፡ በቀኝ ፡ እጁ ፡ ጢሙን ፡
፲፤ ያዘው ፡፡ አሜሳይ ፡ ግን ፡ በኢዮአብ ፡ እጅ ፡ ከነ
በረው ፡ ሰይፍ ፡ አልተጠነቀቀም ፡ ነበር ፤ ኢዮ
አብም ፡ ሆዱን ፡ ወጋው ፥ አንጀቱንም ፡ በም
ድር ፡ ላይ ፡ዘረገፈው ፤ ሁለተኛም ፡ አልወ
ጋውም ፥ ሞተም ፡፡
ኢዮአብና ፡ ወንድሙ ፡ አቢሳ ፡ የቢክሪን ፡
፲፩፤ ልጅ ፡ ሳቤዔን ፡ አሳደዱ ፡፡ ከኢዮአብም ፡ ብላ
ቴኖች ፡ አንዱ ፡ በአሜሳይ ፡ሬሳ ፡ አጠገብ ፡
ቆሞ ፦ ለኢዮአብ ፡ ወዳጅ ፡ የሚሆን ፡ ለዳ
ዊትም ፡ የሆነ ፡ ሁሉ ፡ ኢዮአብን ፡ ይከተል ፡
፲፪፤ ይል ፡ ነበር ፡፡ አሜሳይም ፡ በመንገድ ፡ መካከል ፡
ወድቆ ፡ በደሙ ፡ ላይ ፡ ይንከባለል ፡ ነበር ፤
ያም ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ የሚመጣ ፡ ሁሉ ፡
ሲቆም ፡ አይቶአልና ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡
ቆመ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ አሜሳይን ፡ ከመንገድ ፡ ላይ ፡
ወደ ፡ እርሻ ፡ ውስጥ ፡ ፈቀቅ ፡ አደረገው ፥ በል
፲፫፤ ብስም ፡ ከደነው ፡፡ ከመንገድ ፡ ራቅ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡
ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ የቢክሪን ፡ ልጅ ፡ ሳቤዔን ፡ ለማ
ሳደድ ፡ ኢዮአብን ፡ ተከትሎ ፡ ያልፍ ፡ ነበር ፡፡
፲፬፤ እርሱ ፡ ግን ፡ ከእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ አቤል ፥ ወደ ፡ ቤትመዓካ ፥ ወደ ፡ ቤሪም ፡
ሁሉ ፡ አለፈ ፤ ሰዎችም ፡ ደግሞ ፡ ተሰብስበው ፡
፲፭፤ ተከተሉት ፡፡ በቤትመዓካ ፡ ባለ ፡ በአቤልም ፡
መጥተው ፡ ከበቡት ፥ በከተማይቱም ፡ ላይ ፡
እስከ ፡ ቅጥርዋ ፡ ድረስ ፡ የአፈርን ፡ ድልድል ፡
ደለደሉ ፤ ቅጥሩንም ፡ ያፈርሱ ፡ ዘንድ ፡ ከኢዮ
አብ ፡ ጋር ፡ የነበሩ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ይደበድቡ ፡
፲፮፤ ነበር ፡፡ ከከተማይቱም ፡ አንዲት ፡ ብልሃተኛ ፡
ሴት ፦ ስሙ ፥ ስሙ ፤ ኢዮአብንም ፦ እነጋ
ርህ ፡ ዘንድ ፡ ወደዚህ ፡ ቅረብ ፡ በሉት ፡ ስትል ፡
፲፯፤ ጮኸች ፡፡ ወደ ፡ እርስዋም ፡ ቀረበ ፤ ሴቲቱም ፦
ኢዮአብ ፡ አንተ ፡ ነህን ? አለች ፡፡ እርሱም ፦
እኔ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ መለሰላት ፡፡ እርስዋም ፦ የባ
ሪያህን ፡ ቃል ፡ ስማ ፡ አለችው ፡፡ እርሱም ፦
፲፰፤ እሰማለሁ ፡ አላት ፡፡ እርስዋም ፦ ቀድሞ ፦
የሚጠይቅ ፡ በአቤል ፡ ዘንድ ፡ ይጠይቅ ፡ ይባል ፡
ነበር ፤ እንዲሁም ፡ ነገሩ ፡ ይፈጸም ፡ ነበር ፡፡
፲፱፤ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ሰላምንና ፡ እውነትን ፡
ከሚወድዱ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ አንተ ፡ በእስራኤል ፡
ያለችውን ፡ ከተማና ፡ እናት ፡ ለማፍረስ ፡ ትሻ
ለህ ፤ ስለ ፡ ምንስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ርስት ፡
፳፤ ትውጣለህ ? ብላ ፡ ተናገረች ፡፡ ኢዮአብም ፡
መልሶ ፦ ይህ ፡ መዋጥና ፡ ማጥፋት ፡ ከእኔ ፡
፳፩፤ ይራቅ ፤ ነገሩ ፡ እንዲህ ፡ አይደለም ፤ ከተራራ
ማው ፡ ከኤፍሬም ፡ አገር ፡ የሚሆን ፡ የቢክሪ ፡
ልጅ ፡ ሳቤዔ ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ግን ፡
በንጉሡ ፡ በዳዊት ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ አንሣ ፤ እር
ሱን ፡ ብቻውን ፡ ስጡኝ ፥ እኔም ፡ ከከተማይቱ ፡
እርቃለሁ ፡ አላት ፡፡ ሴቲቱም ፡ ኢዮአብን ፦
እነሆ ፥ ራሱ ፡ ከቅጥር ፡ ላይ ፡ ይጣልልሃል ፡ አለ
፳፪፤ ችው ፡፡ ሴቲቱም ፡ በብልሃትዋ ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡
ሁሉ ፡ ሄደች ፤ እነርሱም ፡ የቢክሪን ፡ ልጅ ፡ የሳ
ቤዔን ፡ ራስ ፡ ቈርጠው ፡ ወደ ፡ ኢዮአብ ፡
ጣሉት ፡፡ እርሱም ፡ ቀንደ ፡ መለከቱን ፡ ነፋ ፥
ሰውም ፡ ሁሉ ፡ ከከተማይቱ ፡ ርቆ ፡ እያንዳንዱ ፡
ወደ ፡ ድንኳኑ ፡ ሄደ ፡፡ ኢዮአብም ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሰ ፡፡
፳፫፤ ኢዮአብም ፡ በእስራኤል ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ አለቃ ፡ ነበረ ፤ የዮዳሄም ፡ ልጅ ፡ በናያስ ፡
በከሊታውያንና ፡ በፈሊታውያን ፡ ላይ ፡ ነበረ ፤
፳፬፤ አዶኒራምም ፡ግብር ፡ አስገባሪ ፡ ነበረ ፤ የአሒ
ሉድም ፡ ልጅ ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ ታሪክ ፡ ጸሐፊ ፡
፳፭፤ ነበረ ፤ ሱሳም ፡ ጸሐፊ ፡ ነበረ ፤ ሳዶቅና ፡ አብ
፳፮፤ ያታርም ፡ ካህናት ፡ ነበሩ ፤ የኢያዕር ፡ ሰውም ፡
ዒራስ ፡ ለዳዊት ፡ አማካሪ ፡ ነበረ ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ በዳዊትም ፡ ዘመን ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡
ቀጥሎ ፡ ቀጥሎ ፡ ራብ ፡ ሆነ ፤ ዳዊትም ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ፊት ፡ ጠየቀ ። እግዚአብሔ
ርም ፦ የገባዖንን ፡ ሰዎች ፡ ስለ ፡ ገደለ ፡ በሳኦ
፪ ልና ፡ በቤቱ ፡ ላይ ፡ ደም ፡ አለበት ፡ አለ ። ንጉ
ሡም ፡ የገባዖንን ፡ ሰዎች ፡ ጠራ ፤ የገባዖን ፡
ሰዎችም ፡ ከአሞራውያን ፡ የተረፉ ፡ ነበሩ ፡ እንጂ ፡
ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ አልነበሩም ፤ የእ
ስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ምለውላቸው ፡ ነበር ፤
ሳኦል ፡ ግን ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆችና ፡ ለይሁዳ ፡
፫ ስለ ፡ ቀና ፡ ሊገድላቸው ፡ ወድዶ ፡ ነበር ። ዳዊ
ትም ፡ የገባዖንን ፡ ሰዎች ፦ የእግዚአብሔርን ፡
ርስት ፡ ትባርኩ ፡ ዘንድ ፡ ምን ፡ ላድርግላችሁ ?
ማስተስረያውስ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አላቸው ።
፬ የገባዖን ፡ ሰዎችም ፦ በእኛና ፡ በሳኦል ፡ ወይም ፡
በእኛና ፡ በቤቱ ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ የብርና ፡
የወርቅ ፡ ነገር ፡ አይደለም ፤ ከእስራኤልም ፡
ወገን ፡ እኛ ፡ የምንገድለው ፡ የለም ፡ አሉት ።
እርሱም ፦ የምትናገሩትን ፡ አደርግላችኋለሁ ፡
፭ አለ ። ንጉሡንም ፦ እኛን ፡ ካጠፋ ÷ በእስራኤ
ልም ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ እንዳንቀመጥ ፡ መፍረሳች
፮ ንን ፡ ካሰበው ፡ ሰው ፡ ልጆች ፡ ሰባት ፡ ሰዎች ፡
አሳልፈህ ፡ ስጠንና ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በተመረ
ጠው ፡ በሳኦል ፡ አገር ፡ በጊብዓ ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ እንሰቅላቸዋለን ፡ አሉት ። ንጉሡም ፦
እሰጣችኋለሁ ፡ አለ ።

፯ ንጉሡም ፡ በሳኦል ፡ ልጅ ፡ በዮናታንና ፡ በዳ
ዊት ፡ መካከል ፡ ስለ ፡ ነበረው ፡ ስለ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ መሐላ ፡ የሳኦልን ፡ ልጅ ፡ የዮናታንን ፡
፰ ልጅ ፡ ሜምፊቦስቴን ፡ አዳነ ። ንጉሡም ፡ ለሳ
ኦል ፡ የወለደቻቸውን ፡ የኢዮሄል ፡ ልጅ ፡ የሪ
ጽፋን ፡ ሁለቱን ፡ ልጆች ፡ ሄርሞንንና ፡ ሜምፊ
ቦስቴን ፡ ለመሐላታዊውም ፡ ለቤርዜሊ ፡ ልጅ ፡
ለኤስድሪኤል ፡ የወለደቻቸውን ፡ የሳኦልን ፡
ልጅ ፡ የሜሮብን ፡ አምስቱን ፡ ልጆች ፡ ወሰደ ÷
፱ ለገባዖንም ፡ ሰዎች ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፤
በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ በተራራው ፡ ላይ ፡
ሰቀሉአቸው ÷ ሰባቱም ፡ በአንድነት ፡ ወደቁ ፤
እህል ፡ በሚታጨድበት ፡ ወራት ፡ በገብሱ ፡
መከር ፡ መጀመሪያ ፡ ተገደሉ ።

፲ የኢዮሄልም ፡ ልጅ ፡ ሪጽፋ ፡ ማቅ ፡ ወስዳ ፡
ከመከር ፡ ወራት ፡ ጀምሮ ፡ ዝናብ ፡ ከሰማይ ፡
እስኪዘንብ ፡ ድረስ ፡ በድንጋይ ፡ ላይ ፡ ዘረጋ
ችው ፡ በቀንም ፡ ወፎች ፡ በሌሊትም ፡ አራዊት ፡
፲፩ ያርፉባቸው ፡ ዘንድ ፡ አልተወችም ። የሳኦልም ፡
ቁባት ፡ የኢዮሄል ፡ ልጅ ፡ ሪጽፋ ፡ ያደረገች
፲፪ ውን ፡ ለዳዊት ፡ ነገሩት ። ዳዊትም ፡ ሄደ ÷
ሳኦልንም ፡ በጊልቦዓ ፡ በገደሉ ፡ ጊዜ ፡ ፍልስጥ
ኤማውያን ፡ ከሰቀሉአቸው ፡ ስፍራ ፡ ከቤትሳን ፡
አደባባይ ፡ ከሰረቁት ፡ ከኢያቢስ ፡ ገለዓድ ፡
ሰዎች ፡ የሳኦልንና ፡ የልጁን ፡ የዮናታንን ፡ አጥ
፲፫ ንት ፡ ወሰደ ፤ ከዚያም ፡ የሳኦልንና ፡ የልጁን ፡
የዮናታንን ፡ አጥንት ፡ ይዞ ፡ መጣ ፤ የተሰቀሉ
፲፬ ትንም ፡ ሰዎች ፡ አጥንት ፡ ሰበሰቡ ። የሳኦልንና ፡
የልጁን ፡ የዮናታንን ፡ አጥንት ፡ በብንያም ፡
አገር ፡ በጼላ ፡ በአባቱ ፡ በቂስ ፡ መቃብር ፡ ቀበ
ሩት ፤ ንጉሡም ፡ ያዘዘውን ፡ ሁሉ ፡ አደረጉ ።
ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ አገሩ ፡
የተለመነውን ፡ ሰማ ።

፲፭ በፍልስጥኤማውያንና ፡ በእስራኤልም ፡ መካ
ከል ፡ ደግሞ ፡ ሰልፍ ፡ ነበረ ፤ ዳዊትም ፡ ከእር
ሱም ፡ ጋር ፡ ባሪያዎቹ ፡ ወረዱ ÷ ከፍልስጥኤማ
ውያንም ፡ ጋር ፡ ተዋጉ ፤ ዳዊትም ፡ ደከመ ።
፲፮ ከራፋይም ፡ ወገን ፡ የነበረው ፡ ይሽቢብኖብ ፡ ዳዊ
ትን ፡ ይገድል ፡ ዘንድ ፡ አሰበ ፤ የጦሩም ፡ ሚዛን ፡
ክብደት ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሰቅል ፡ ናስ ፡ ነበረ ÷
፲፯ አዲስም ፡ የጦር ፡ መሣርያ ፡ ታጥቆ ፡ ነበር ። የጽ
ሩያም ፡ ልጅ ፡ አቢሳ ፡ አዳነው ÷ ፍልስጥኤማ
ዊውንም ፡ መትቶ ፡ ገደለው ። ያንጊዜም ፡ የዳ
ዊት ፡ ሰዎች ፦ አንተ ፡ የእስራኤልን ፡ መብ
ራት ፡ እንዳታጠፋ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ከእኛ ፡
ጋር ፡ ለሰልፍ ፡ አትወጣም ፡ ብለው ፡ ማሉለት ።

፲፰ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ በጎብ ፡ ላይ ፡
ከፍልስጥኤማውያን ፡ ጋር ፡ ሰልፍ ፡ ሆነ ÷ ኩሳ
ታዊውም ፡ ሴቦካይ ፡ ከራፋይም ፡ ወገን ፡ የነበ
፲፱ ረውን ፡ ሳፍን ፡ ገደለ ። ደግሞም ፡ በጎብ ፡ ላይ ፡
ከፍልስጥኤማውያን ፡ ጋር ፡ ሰልፍ ፡ ነበረ ፤
የቤተ ፡ ልሔማዊውም ፡ የየዓሬኦርጊም ፡ ልጅ ፡
ኤልያናን ፡ የጦሩ ፡ የቦ ፡ እንደ ፡ ሸማኔ ፡ መጠቅ
ለያ ፡ የነበረውን ፡ የጌት ፡ ሰው ፡ ጎልያድን ፡
፳ ገደለ ። ደግሞም ፡ በጌት ፡ ላይ ፡ ሰልፍ ፡ ሆነ ፤
በዚያም ፡ በእጁና ፡ በእግሩ ፡ ስድስት ፡ ስድስት ፡
ሁላሁሉ ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ጣቶች ፡ የነበሩት ፡ አንድ ፡
ረጅም ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ ከራፋ
፳፩ ይም ፡ የተወለደ ፡ ነበረ ። እስራኤልንም ፡ በተ
ገዳደረ ፡ ጊዜ ፡ የዳዊት ፡ ወንድም ፡ የሣማ ፡ ልጅ ፡
፳፪ ዮናታን ፡ ገደለው ። እነዚያም ፡ አራቱ ፡ በጌት ፡
ውስጥ ፡ ከራፋይም ፡ የተወለዱ ፡ ነበሩ ፤ በዳዊ
ትም ፡ እጅ ፡ በባሪያዎቹም ፡ እጅ ፡ ወደቁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ ዳዊትም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሳኦል ፡ እጅና ፡
ከጠላቶቹ ፡ እጅ ፡ ሁሉ ፡ ባዳነው ፡ ቀን ፡ የዚህን ፡
፪ ቅኔ ፡ ቃል ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተናገረ ። እንዲ
ህም ፡ አለ ፦

እግዚአብሔር ፡ ዓለቴ ፡ አምባዬ ፡ መድኃ
ኒቴ ፡ ነው ፤
፫ እግዚአብሔር ፡ ጠባቂዬ ፡ ነው ÷ በእርሱም ፡
እታመናለሁ ፤
ጋሻዬና ፡ የረድኤቴ ፡ ቀንድ ÷ መጠጊያዬና ፡
መሸሸጊያዬ ÷
መድኃኒቴ ፡ ሆይ ÷ ከግፍ ፡ ሥራ ፡ ታድነ
ኛለህ ።
፬ ምስጋና ፡ የሚገባውን ፡ እግዚአብሔርን ፡
እጠራለሁ ፤
ከጠላቶቼም ፡ እድናለሁ ።

፭፤ የሞት ፡ ጣር ፡ ያዘኝ ፤
የዓመፅ ፡ ፈሳሽም ፡ አስፈራኝ ፤
፮፤ የሲኦል ፡ ጣር ፡ ከበበኝ ፤
የሞት ፡ ወጥመድ ፡ ደረሰብኝ ።
፯፤ በጨነቀኝ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠራሁት ፥
ወደ ፡ አምላኬም ፡ ጮኽሁ ፤
ከመቅደሱም ፡ ቃሌን ፡ ሰማኝ ፥
ጩኸቴም ፡ በፊቱ ፡ ወደ ፡ ጆሮው ፡ ገባ ።
፰፤ ምድርም ፡ ተንቀጠቀጠች ፥ ተናወጠችም ፥
የሰማዮችም ፡ መሠረቶች ፡ ተንቃነቁ ፤
እግዚአብሔርም ፡ ተቈጥቶአልና ፡ ተንቀጠቀጡ ።
፱፤ ከቍጣው ፡ ጢስ ፡ ወጣ ፥
ከአፉም ፡ የሚበላ ፡ እሳት ፡ ነደደ ፤
ፍምም ፡ ከእርሱ ፡ በራ ።
፲፤ ሰማዮችን ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አደረገ ፥ ወረደም ፤
ጨለማም ፡ ከእግሩ ፡ በታች ፡ ነበረ ።
፲፩፤ በኪሩብም ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ በረረ ፤
በነፋስም ፡ ክንፍ ፡ ሆኖ ፡ ታየ ፤
፲፪፤ መሰወርያውን ፡ ጨለማ ፥
በዙሪያውም ፡ የነበረውን ፡ ድንኳን ፥
በደመና ፡ ውስጥ ፡ የነበረ ፡ የጨለማ ፡ ውኃ ፡ አደረገ ።
፲፫፤ በፊቱም ፡ ካለው ፡ ብርሃን ፡ የተነሣ ፡ ፍም ፡ ተቃጠለ ።
፲፬፤ እግዚአብሔርም ፡ ከሰማያት ፡ አንጐደጐደ ፥
ልዑልም ፡ ቃሉን ፡ ሰጠ ፤
፲፭፤ ፍላጻውን ፡ ላከ ፥ በተናቸውም ፤
መብረቆችን ፡ ላከ ፥ አወካቸውም ።
፲፮፤ ከእግዚአብሔር ፡ ዘለፋ ፥
ከመዓቱም ፡ መንፈስ ፡ እስትንፋስ ፡ የተነሣ ፥
የባሕር ፡ ፈሳሾች ፡ ታዩ ፥
የዓለም ፡ መሠረቶችም ፡ ተገለጡ ።
፲፯፤ ከላይ ፡ ሰደደ ፥ ወሰደኝም ፤
ከብዙ ፡ ውኆችም ፡ አወጣኝ ።
፲፰፤ ከብርቱዎች ፡ ጠላቶቼ ፥
ከሚጠሉኝም ፡ አዳነኝ ፤ በርትተውብኝ ፡ ነበርና ።
፲፱፤ በመከራዬ ፡ ቀን ፡ ደረሱብኝ ፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ደገፋዬ ፡ ሆነ ።
፳፤ ወደ ፡ ሰፊ ፡ ስፍራም ፡ አወጣኝ ፤
ወድዶኛልና ፡ አዳነኝ ።
፳፩፤ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ጽድቄ ፡ ይከፍለኛል ፤
እንደ ፡ እጄ ፡ ንጽሕና ፡ ይመልስልኛል ፤
፳፪፤ የእግዚአብሔርን ፡ መንገድ ፡ ጠብቄአለሁና ፥
በአምላኬም ፡ አላመፅሁምና ።
፳፫፤ ፍርዱ ፡ ሁሉ ፡ በፊቴ ፡ ነበረና ፤
ከሥርዓቱም ፡ አልራቅሁምና ።
፳፬፤ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ቅን ፡ ነበርሁ ፥
ከኃጢአቴም ፡ ተጠበቅሁ ።
፳፭፤ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ጽድቄ ፥
እንደ ፡ እጄም ፡ ንጽሕና ፡ በዓይኖቹ ፡ ፊት ፡ መለሰልኝ ።
፳፮፤ ከቸር ፡ ሰው ፡ ጋር ፡ ቸር ፡ ሆነህ ፡ ትገኛለህ ፤
ከቅን ፡ ሰው ፡ ጋር ፡ ቅን ፡ ሆነህ ፡ ትገኛለህ ፤
፳፯፤ ከንጹሕ ፡ ጋር ፡ ንጹሕ ፡ ሆነህ ፡ ትገኛለህ ፤
ከጠማማም ፡ ጋር ፡ ጠማማ ፡ ሆነህ ፡ ትገኛለህ ።
፳፰፤ አንተ ፡ የተጠቃውን ፡ ሕዝብ ፡ ታድናለህና ፤
የትዕቢተኞችን ፡ ዓይን ፡ ግን ፡ ታዋርዳለህ ።
፳፱፤ አቤቱ ፥ አንተ ፡ መብራቴ ፡ ነህና ፤
እግዚአብሔርም ፡ ጨለማዬን ፡ ያበራል ።
፴፤ በአንተ ፡ ኃይል ፡ በጭፍራ ፡ ላይ ፡ እሮጣለሁና ፤
በአምላኬም ፡ ቅጥሩን ፡ እዘልላለሁና ።
፴፩፤ የአምላክ ፡ መንገድ ፡ ፍጹም ፡ ነው ፤
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ የነጠረ ፡ ነው ፤
በእርሱ ፡ ለሚታመኑት ፡ ሁሉ ፡ ጋሻ ፡ ነው ።
፴፪፤ ከእግዚአብሔር ፡ በቀር ፡ አምላክ ፡ ማን ፡ ነው ?
ከአምላካችንስ ፡ በቀር ፡ አምባ ፡ ማን ፡ ነው ?
፴፫፤ ኃይልን ፡ የሚያስታጥቀኝ ፥ መንገዴንም ፡ የሚያቃና ፥
፴፬፤ እግሮቼን ፡ እንደ ፡ ብሆር ፡ እግሮች ፡ የሚያረታ ፥
በኮረብቶችም ፡ የሚያቆመኝ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ።
፴፭፤ እጆቼን ፡ ሰልፍ ፡ ያስተምራል ፤
በክንዴም ፡ የናስ ፡ ቀስት ፡ እገትራለሁ ።
፴፮፤ የማዳንህንም ፡ ጋሻ ፡ ሰጠኸኝ ፤
ተግሣጽህም ፡ አሳደገኝ ።
፴፯፤ አረማመዴን ፡ በበታቼ ፡ አሰፋህ ፥
እግሮቼም ፡ አልተንሸራተቱም ።
፴፰፤ ጠላቶቼን ፡ አሳድዳቸዋለሁ ፥ አጠፋቸውማለሁ ፤
እስካጠፋቸውም ፡ ድረስ ፡ አልመለስም ።
፴፱፤ አስጨንቃቸዋለሁ ፡ መቆምም ፡ አይችሉም ፥
ከእግሬም ፡ በታች ፡ ይወድቃሉ ።
፵፤ ለሰልፍም ፡ ኃይልን ፡ ታስታጥቀኛለህ ፤
በላዬ ፡ የቆሙትን ፡ በበታቼ ፡ ታስገዛቸዋለህ ።
፵፩፤ የጠላቶቼን ፡ ጀርባ ፡ ሰጠኸኝ ፥
የሚጠሉኝንም ፡ አጠፋሃቸው ።
፵፪፤ ጮኹ ፥ የሚረዳቸውም ፡ አልነበረም ፤
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ፥ አልሰማቸውምም ።
፵፫፤ እንደ ፡ ምድር ፡ ትቢያ ፡ ፈጨኋቸው ፤
እንደ ፡ አደባባይም ፡ ጭቃ ፡ ረገጥኋቸው ፥ ደቀደቅኋቸውም ።
፵፬፤ ከሕዝብ ፡ ክርክር ፡ ታድነኛለህ ፤
የአሕዛብም ፡ ራስ ፡ አድርገህ ፡ ትሾመኛለህ ፤
የማላውቀው ፡ ሕዝብም ፡ ይገዛልኛል ።
፵፭፤ የባዕድ ፡ ልጆች ፡ ደለሉኝ ፤
በጆሮ ፡ ሰምተው ፡ ተገዙልኝ ።

፵፮ የባዕድ ፡ ልጆች ፡ እየጠፉ ፡ ይሄዳሉ ፤
ከተዘጉ ፡ ስፍሮች ፡ እየተንቀጠቀጡ ፡ ይወ
ጣሉ ።
፵፯ እግዚአብሔር ፡ ሕያው ፡ ነው ፥ ጠባቂዬም ፤
ቡሩክ ፡ ነው ፤
የመድኃኒቴ ፡ ጠባቂ ፡ አምላኬ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡
ይበል ፤
፵፰ በቀሌን ፡ የሚመልስልኝ ፡ አምላክ ፥
አሕዛብን ፡ በበታቼ ፡ የሚያስገዛ ፥
፵፱ ከጠላቶቼ ፡ የሚያወጣኝ ፡ እርሱ ፡ ነው ፤
በእኔም ፡ ላይ ፡ ከቆሙ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ታደ
ርገኛለህ ፤
ከግፈኛ ፡ ሰው ፡ ታድነኛለህ ።
፶ አቤቱ ፥ ስለዚህ ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ አመሰ
ግንሃለሁ ፥
ለስምህም ፡ እዘምራለሁ ።
፶፩ የንጉሡን ፡ መድኃኒት ፡ ታላቅ ፡ ያደርጋል ፤
ቸርነቱንም ፡ ለቀባው ፥ ለዳዊትና ፡ ለዘሩ ፥
ለዘላለም ፡ ይሰጣል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ የዳዊትም ፡ የመጨረሻ ፡ ቃሉ ፡ ይህ ፡ ነው ።
ከፍ ፡ ከፍ ፡ የተደረገው ፥ በያዕቆብም ፡ አም
ላክ ፡ የተቀባው ፥
በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ መልክም ፡ ባለ ፡ ቅኔ ፡
የሆነ ፥
የእሴይ ፡ ልጅ ፡ የዳዊት ፡ ንግግር ፤
፪ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ በእኔ ፡ ተናገረ ፤
ቃሉም ፡ በአንደበቴ ፡ ላይ ፡ ነበረ ።
፫ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ተናገረኝ ፤
የእስራኤል ፡ ጠባቂ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦
በሰው ፡ ላይ ፡ በጽድቅ ፡ የሚሠለጥን ፥
በእግዚአብሔርም ፡ ፍርሃት ፡ የሚነግሥ ፥
፬ እርሱ ፡ እንደ ፡ ማለዳ ፡ ብርሃን ፡ እንደ ፡
ፀሐይ ፡ አወጣጥ ፥
በጥዋትም ፡ ያለ ፡ ደመና ፡ እንደሚደምቅ ፥
ከዝናብ ፡ በኋላ ፡ ከምድር ፡ እንደሚበቅል ፡
ልምላሜ ፡ ይሆናል ።
፭ በውኑ ፡ ቤቴ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
እንዲሁ ፡ አይደለምን ?
ከእኔም ፡ ጋር ፡ በሁሉ ፡ ነገር ፡ ቅንና ፡ ጽኑ ፡
የሆነውን ፡
የዘላለም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አድርጎአል ፤
መድኃኒቴንና ፡ ፈቃዴን ፡ ሁሉ ፡ ያበቅላል ።
፮ ዓመፀኞች ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ሰው ፡ በእጁ ፡ እን
ደማይዘው ፥
እንደ ፡ ተጣለ ፡ እሾህ ፡ ናቸው ።
፯ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ይነካው ፡ ዘንድ ፡ ቢወ
ድድ ፥
በእጁ ፡ ብረትና ፡ የጦሩን ፡ የቦ ፡ ይይዛል ፤
በሥራቸውም ፡ በእሳት ፡ ፈጽሞ ፡ ይቃጠ
ላሉ ።
፰ የዳዊት ፡ ኃያላን ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ። የአለ
ቆች ፡ አለቃ ፡ የሆነ ፡ ከነዓናዊው ፡ ኢያቡስቴ ፡
ነበረ ፤ እርሱም ፡ ጦሩን ፡ አንሥቶ ፡ ስምንት ፡
መቶ ፡ ያህል ፡ በአንድ ፡ ጊዜ ፡ ገደለ ።

፱ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ የአሆሃዊው ፡ የዱዲ ፡
ልጅ ፡ ኤልያናን ፡ ነበረ ፤ ለሰልፍ ፡ የተሰበሰቡ
ትን ፡ ፍልስጥኤማውያንን ፡ በተገዳደሩ ፡ ጊዜ ፡
ከዳዊት ጋር ፡ ከሦስቱ ፡ ኃያላን ፡ አንዱ ፡ እርሱ ፡
ነበረ ፤ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ተመለሱ ። ፲ እርሱ ፡
ግን ፡ ተነሥቶ ፡ እጁ ፡ እስኪደክምና ፡ ከሰይፉ ፡
ጋር ፡ እስኪጣበቅ ፡ ድረስ ፡ ፍልስጥኤማውያ
ንን ፡ መታ ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡
ታላቅ ፡ መድኃኒት ፡ አደረገ ፤ ሕዝቡም ፡ ከእ
ርሱ ፡ በኋላ ፡ ምርኮ ፡ ለመግፈፍ ፡ ብቻ ፡ ተመ
ለሰ ።

፲፩ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ የአሮዳዊው ፡ የአጌ ፡ ልጅ ፡
ሣማ ፡ ነበረ ። ፍልስጥኤማውያንም ፡ ምስር ፡
በሞላበት ፡ እርሻ ፡ በአንድነት ፡ ሆነው ፡ ተከማ
ችተው ፡ ነበር ፤ ሕዝቡም ፡ ከፍልስጥኤማው
ያን ፡ ፊት ፡ ሸሹ ። ፲፪ እርሱ ፡ ግን ፡ በእርሻው ፡
መካከል ፡ ቆሞ ፡ ጠበቀ ፥ ፍልስጥኤማውያን
ንም ፡ ገደለ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ታላቅ ፡ መድ
ኃኒት ፡ አደረገ ።

፲፫ ከሠላሳውም ፡ አለቆች ፡ ሦስቱ ፡ ወርደው ፡
በመከር ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ወደ ፡ ዓዶላም ፡
ዋሻ ፡ መጡ ፤ የፍልስጥኤማውያንም ፡ ጭፍራ ፡
በራፋይም ፡ ሸለቆ ፡ ሰፍሮ ፡ ነበር ። ፲፬ በዚያ ፡
ጊዜም ፡ ዳዊት ፡ በምሽጉ ፡ ውስጥ ፡ ነበረ ፥ የፍ
ልስጥኤማውያንም ፡ ጭፍራ ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡
በቤተ ፡ ልሔም ፡ ነበረ ። ፲፭ ዳዊትም ፦ በበሩ ፡
አጠገብ ፡ ካለችው ፡ ከቤተ ፡ ልሔም ፡ ምንጭ ፡
ውኃ ፡ ማን ፡ ባጠጣኝ ? ብሎ ፡ ተመኘ ። ፲፮ ሦስቱም ፡
ኃያላን ፡ የፍልስጥኤማውያንን ፡ ሠራዊት ፡ ቀድ
ደው ፡ ሄዱ ፥ በበሩም ፡ አጠገብ ፡ ካለችው ፡
ከቤተ ፡ ልሔም ፡ ምንጭ ፡ ውኃ ፡ ቀዱ ፥ ይዘ
ውም ፡ ለዳዊት ፡ አመጡለት ፤ እርሱ ፡ ግን ፡
ሊጠጣ ፡ አልወደደም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ለእግዚአ
ብሔር ፡ አፍስሶ ፦ ፲፯ አቤቱ ፥ ይህን ፡ አደርግ ፡
ዘንድ ፡ ከእኔ ፡ ይራቅ ፤ በነፍሳቸው ፡ ደፍረው ፡
የሄዱ ፡ ሰዎች ፡ ደም ፡ አይደለምን ? ብሎ ፡
ይጠጣ ፡ ዘንድ ፡ አልወደደም ። ሦስቱ ፡ ኃያላን ፡
ያደረጉት ፡ ይህ ፡ ነው ።

፲፰ የጽሩያም ፡ ልጅ ፡ የኢዮአብ ፡ ወንድም ፡
አቢሳ ፡ የሠላሳው ፡ አለቃ ፡ ነበረ ። እርሱም ፡
ጦሩን ፡ በሦስቱ ፡ መቶ ፡ ላይ ፡ አንሥቶ ፡ ገደላ
ቸው ፤ ስሙም ፡ እንደ ፡ ሦስቱ ፡ ተጠርቶ ፡ ነበር ።
፲፱ እርሱ ፡ በሠላሳው ፡ መካከል ፡ የከበረ ፡ አልነበ
ረምን ? ስለዚህም ፡ አለቃቸው ፡ ሆኖ ፡ ነበር ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ሦስቱ ፡ አልደረሰም ።

፳ በቀብጽኤል ፡ የነበረው ፡ ታላቅ ፡ ሥራ ፡ ያደ
ረገው ፡ የጽኑዕ ፡ ሰው ፡ የዮዳሄ ፡ ልጅ ፡ በናያስ ፡
የሞዓባዊውን ፡ የቀብስኤልን ፡ ሁለት ፡ ልጆች ፡
ገደለ ፤ በአመዳዩም ፡ ወራት ፡ ወርዶ ፡ በጕድ
ጓድ ፡ ውስጥ ፡ አንበሳ ፡ ገደለ ። ፳፩ ረጅሙንም ፡
ግብጻዊ ፡ ሰው ፡ ገደለ ፤ ግብጻዊው ፡ በእጁ ፡
ጦር ፡ ነበረው ፤ በናያስ ፡ ግን ፡ በትር ፡ ይዞ ፡

ወደ ፡ እርሱ ፡ ወረደ ÷ ከግብጻዊውም ፡ እጅ ፡ ጦሩን ፡ ነቅሎ ፡ በገዛ ፡ ጦሩ ፡ ገደለው ። ፳፪ የዮዳሄ ፡ ልጅ ፡ በናያስ ፡ ያደረገው ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ስሙም ፡ እንደ ፡ ሦስቱ ፡ ኃያላን ፡ ተጠርቶ ፡ ነበር ። ፳፫ ከሠላሳውም ፡ ይልቅ ፡ የከበረ ፡ ነበረ ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ሦስቱ ፡ አልደረሰም ። ዳዊትም ፡ በክብር ፡ ዘበኞቹ ፡ ላይ ፡ ሾመው ።

፳፬ የኢዮአብም ፡ ወንድም ፡ አሣሄል ፡ በሠላሳው ፡ መከከል ፡ ነበረ ÷ የቤተ ፡ ልሔም ፡ ሰው ፡ የዱዲ ፡ ፳፭ ልጅ ፡ ኤልያናን ÷ አሮዳዊው ፡ ሣማ ÷ ሐሮዳ ፳፮ ዊው ፡ ኤሊቃ ÷ ፈልጣዊው ፡ ሴሌስ ÷ የቴቁሐ ፳፯ ዊው ፡ የዒስካ ፡ ልጅ ፡ ዒራስ ÷ ዓናቶታዊው ፡ ፳፰ አቢዔዜር ÷ ኩሳታዊው ፡ ምቡናይ ÷ አሆሃ ፳፱ ዊው ፡ ጸልሞን ÷ ነጦፋዊው ፡ ኖኤሬ ÷ የነጦ ፋዊው ፡ የበዓና ፡ ልጅ ፡ ሔሌብ ÷ ከብንያም ፡ ፴ ወገን ፡ ከጊብዓ ፡ የሪባይ ፡ ልጅ ፡ ኢታይ ÷ ጲር ዓቶናዊው ፡ በናያስ ÷ የገዓስ ፡ ወንዝ ፡ ሰው ፡ ፴፩ ሂዳይ ÷ ዓረባዊው ፡ አቢዓልቦን ÷ በርሑማ ፴፪ ዊው ፡ ዓዝሞት ÷ ሸዓልቦናዊው ፡ ኤሊያሕባ ÷ ፴፫ የአሳን ፡ ልጆች ÷ ዮናታን ÷ አሮዳዊው ፡ ሣማ ÷ ፴፬ የአሮዳዊው ፡ የአራር ፡ ልጅ ፡ አምናን ÷ የማዕ ከታዊው ፡ ልጅ ፡ የአሐስባይ ፡ ልጅ ፡ ኤሌፋላት ÷ የጊሎናዊው ፡ የአኪጦፌል ፡ ልጅ ፡ ኤልያብ ÷ ፴፭ ቀርሜሎሳዊው ፡ ሐጽሮ ÷ አርባዊው ፡ ፈዓራይ ÷ ፴፮ የሱባ ፡ ሰው ፡ የናታን ፡ ልጅ ፡ ይግዓል ÷ ጋዳ ፴፯ ዊው ፡ ባኒ ÷ የጽሩያ ፡ ልጅ ፡ የኢዮአብ ፡ ጋሻ ፡ ጃግሬዎች ፡ አሞናዊው ፡ ጼሌቅ ÷ ብኤሮታዊው ፡ ፴፰ ነሃራይ ÷ ይትራዊው ፡ ዒራስ ÷ ይትራዊው ፡ ፴፱ ጋሬብ ÷ ኬጢያዊው ፡ ኦርዮ ፤ ሁሉ ፡ በሁሉ ፡ ሠላሳ ፡ ሰባት ፡ ናቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ ደግሞም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በእስራ ኤል ፡ ላይ ፡ ነደደ ÷ ዳዊትንም ፡— ሂድ ÷ እስራ ኤልንና ፡ ይሁዳን ፡ ቍጠር ፡ ብሎ ፡ በላያቸው ፡ ፪ አስነሣው ። ንጉሡም ፡ ኢዮአብንና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩትን ፡ የሠራዊት ፡ አለቆች ፡— የሕ ዝቡን ፡ ድምር ፡ አውቅ ፡ ዘንድ ፡ ከዳን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ቤርሳቤህ ፡ ድረስ ፡ ተመላለሱ ÷ ሕዝቡ ፫ ንም ፡ ቍጠሩአቸው ፡ አላቸው ። ኢዮአብም ፡ ንጉሡን ፡— የጌታዬ ፡ የንጉሡ ፡ ዓይን ፡ እያየ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዛሬ ፡ ካለው ፡ ሕዝብ ፡ መጠን ፡ በላይ ፡ መቶ ፡ እጥፍ ፡ ይጨምርበት ፤ ጌታዬ ፡ ንጉሡ ፡ ግን ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ለምን ፡ ይወ ፬ ድዳል ? አለው ። ነገር ፡ ግን ፡ የንጉሡ ፡ ቃል ፡ በኢዮአብና ፡ በሠራዊቱ ፡ አለቆች ፡ ላይ ፡ አሸ ነፈ ። ኢዮአብና ፡ የሠራዊቱ ፡ አለቆችም ፡ የእስ ራኤልን ፡ ሕዝብ ፡ ይቈጥሩ ፡ ዘንድ ፡ ከንጉሥ ፡ ፭ ዘንድ ፡ ወጡ ። ዮርዳኖስንም ፡ ተሻገሩ ፤ በጋድ ፡ ሸለቆ ፡ መከከል ፡ ባለችው ፡ በኢያዜር ፡ ከተማ ፡ ፮ ቀኝ ፡ በኩል ፡ በአሮዔር ፡ ላይ ፡ ሰፈሩ ። ወደ ፡ ገለዓድም ፡ ወደ ፡ ተበሰን ፡ አዳስይ ፡ አገር ፡ መጡ ፤ ወደ ፡ ዳንየዓንም ፡ ደረሱ ÷ ወደ ፡ ሲዶናም ፡ ፯ ዞሩ ÷ ወደ ፡ ጢሮስም ፡ ምሽግ ፡ ወደ ፡ ኤዊያው ያንና ፡ ወደ ፡ ከነዓናውያንም ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ መጡ ፤ በይሁዳም ፡ ደቡብ ፡ በኩል ፡ በቤርሳ ቤህ ፡ ወጡ ። ፰ በአገሪቱም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ተመላ ልሰው ፡ ከዘጠኝ ፡ ወርና ፡ ከሀያ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጡ ። ፱ ኢዮአብም ፡ የሕ ዝቡን ፡ ቍጥር ፡ ድምር ፡ ለንጉሡ ፡ ሰጠ ፤ በእ ስራኤልም ፡ ሰይፍ ፡ የሚመዝዙ ፡ ስምንት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ ጽኑዓን ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ የይሁ ዳም ፡ ሰዎች ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ ነበሩ ።

፲ ሕዝቡንም ፡ ከቈጠረ ፡ በኋላ ፡ ዳዊትን ፡ ልቡ ፡ መታው ፤ ዳዊትም ፡ እግዚአብሔርን ፡— ባደረ ግሁት ፡ ነገር ፡ እጅግ ፡ በድያለሁ ፤ አሁን ፡ ግን ÷ አቤቱ ÷ ታላቅ ፡ ስንፍና ፡ አድርጌአለሁና ፡ የባ ሪያህን ፡ ኃጢአት ፡ ታርቅ ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃ ለሁ ፡ አለው ። ፲፩ ዳዊትም ፡ ማልዶ ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ÷ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ባለ ፡ ራእይ ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡ ወደ ፡ ጋድ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ፲፪ መጣ ፡— ሂድ ፡ ለዳዊት ፡— እግዚአብሔር ፡ እን ዲህ ፡ ይላል ፡— ሦስት ፡ ነገሮች ፡ በፊትህ ፡ አኖ ራለሁ ፤ አደርግብህ ፡ ዘንድ ፡ ከእነርሱ ፡ አንዱን ፡ ፲፫ ምረጥ ፡ ብለህ ፡ ንገረው ፡ አለው ። ጋድም ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ መጥቶ ፡— የሦስት ፡ ዓመት ፡ ራብ ፡ በአገርህ ፡ ላይ ፡ ይምጣብህን ? ወይስ ፡ ጠላቶ ችህ ፡ እያሳደዱህ ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ ከእነርሱ ፡ ትሸ ሽን ? ወይስ ፡ የሦስት ፡ ቀን ፡ ቸነፈር ፡ በአገርህ ፡ ላይ ፡ ይሁን ? አሁንም ፡ ለላከኝ ፡ ምን ፡ መልስ ፡ እንደምሰጥ ፡ አስብና ፡ መርምር ፡ ብሎ ፡ ነገረው ። ፲፬ ዳዊትም ፡ ጋድን ፡— እጅግ ፡ ተጨንቄአለሁ ፤ ምሕረቱ ፡ ብዙ ፡ ነውና ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ እንውደቅ ፤ በሰው ፡ እጅ ፡ ግን ፡ አልውደቅ ፡ አለው ።

፲፭ ዳዊትም ፡ ቸነፈሩን ፡ መረጠ ፤ የስንዴም ፡ መከር ፡ ወራት ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ቸነፈሩ ፡ በሕዝቡ ፡ መከከል ፡ ጀመረ ፤ ከሕዝቡም ፡ ሰባ ፡ ሺህ ፡ ሰው ፡ ሞተ ። ፲፮ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ያጠፋት ፡ ዘንድ ፡ እጁን ፡ በዘ ረጋ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ክፉው ፡ ነገር ፡ አዘነ ÷ ሕዝቡንም ፡ የሚያጠፋውን ፡ መልአክ ፡— እንግዲህ ፡ በቃህ ፤ እጅህን ፡ መልስ ፡ አለው ። የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ በኢያቡሳዊው ፡ በኦርና ፡ አውድማ ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ። ፲፯ ዳዊትም ፡ ሕዝቡን ፡ የሚመታውን ፡ መልአክ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡— እነሆ ÷ እኔ ፡ በድያለሁ ፡ ጠማማም ፡ ሥራ ፡ እኔ ፡ አድርጌአለሁ ፤ እነዚህ ፡ በጎች ፡ ግን ፡ እነርሱ ፡ ምን ፡ አደረጉ ? እጅህ ፡ በእኔና ፡ በአባቴ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ እንድትሆን ፡ እለ ምንሃለሁ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ።

፲፰ በዚያም ፡ ቀን ፡ ጋድ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ መጥቶ ፡— ውጣ ÷ በኢያቡሳዊው ፡ በኦርና ፡ አውድማ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ሥራ ፡ አለው ። ፲፱ ዳዊትም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ እንደ ፡ ጋድ ፡ ነገር ፡ ወጣ ። ፳ ኦርናም ፡ ሲመለከት ፡ ንጉ ሡና ፡ ባሪያዎቹ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ሲመጡ ፡ አየ ፤ ኦርናም ፡ ወጥቶ ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ በምድር ፡

፳፩፤ ላይ ፡ በግምባሩ ፡ ተደፋ ። ኦርናም ፦ ጌታ
ዬን ፡ ንጉሡን ፡ ወደ ፡ ባሪያው ፡ ያመጣው ፡ ምክ
ንያት ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለ ። ዳዊትም ፦ መቅ
ሠፍቱ ፡ ከሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ይከለከል ፡ ዘንድ ፡ አው
ድማውን ፡ ከአንተ ፡ ገዝቼ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
፳፪፤ መሠዊያ ፡ ልሠራ ፡ ነው ፡ አለው ። ኦርናም ፡
ዳዊትን ፦ ጌታዬ ፡ ንጉሡ ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡
ወስዶ ፡ ያቅርብ ፤ እነሆ ፥ ለሚቃጠል ፡ መሥዋ
ዕት ፡ በሬዎች ፥ ለሚቃጠልም ፡ እንጨት ፡ የአ
፳፫፤ ውድማ ፡ ዕቃና ፡ የበሬ ፡ ቀንበር ፡ አለ ። ንጉሥ ፡
ሆይ ፥ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ኦርና ፡ ለንጉሡ ፡ ይሰጣል ፡
አለው ፤ ኦርናም ፡ ንጉሡን ፦ አምላክህ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ይቀበልህ ፡ አለው ። ንጉሡም ፡ ፳፬፤
ኦርናን ፦ እንዲህ ፡ አይደለም ፥ ነገር ፡ ግን ፡
በዋጋ ፡ ከአንተ ፡ እገዛለሁ ፤ ለአምላኬም ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ያለ ፡
ዋጋ ፡ አላቀርብም ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ አውድ
ማውንና ፡ በሬዎቹን ፡ በአምሳ ፡ ሰቅል ፡ ብር ፡
ገዛ ። በዚያም ፡ ዳዊት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠ ፳፭፤
ዊያ ፡ ሠራ ፥ የሚቃጠልና ፡ የደኅንነትንም ፡
መሥዋዕት ፡ አቀረበ ። እግዚአብሔርም ፡ ስለ ፡
አገሪቱ ፡ የተለመነውን ፡ ሰማ ፥ መቅሠፍቱም ፡
ከእስራኤል ፡ ተከለከለ ።

# መጽሐፈ ፡ ነገሥት ፡ ቀዳማዊ ።

( እርሱም ፡ መጽሐፈ ፡ ነገሥት ፡ ሣልስ ፡ ነው ። )

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ ንጉሡ ፡ ዳዊትም ፡ ሸመገለ ፡ ዕድሜውም ፡
በዛ ፤ ልብስም ፡ ደረቡለት ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አይሞ
፪፤ ቀውም ፡ ነበር ። ባሪያዎቹም ፦ ለጌታችን ፡ ለን
ጉሡ ፡ ድንግል ፡ ትፈለጋለች ፤ በንጉሡም ፡ ፊት ፡
ቆማ ፡ ታገልግለው ፥ በጌታችንም ፡ በንጉሡ ፡
፫፤ ብብት ፡ ተኝታ ፡ ታሙቀው ፡ አሉት ። በእስራ
ኤልም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ የተዋበች ፡ ቈንጆ ፡ ፈለጉ ፤
ሱነማይቱን ፡ አቢሳንም ፡ አገኙ ፥ ወደ ፡ ንጉ
፬፤ ሡም ፡ ይዘዋት ፡ መጡ ። ቈንጆይቱም ፡ እጅግ ፡
ውብ ፡ ነበረች ፤ ንጉሡንም ፡ ትረዳውና ፡ ታገ
ለግለው ፡ ነበር ፥ ንጉሡ ፡ ግን ፡ አያውቃትም ፡
ነበር ።

፭፤ የአጊትም ፡ ልጅ ፡ አዶንያስ ፦ ንጉሥ ፡ እሆና
ለሁ ፡ ብሎ ፡ ተነሣ ፤ ሰረገሎችንና ፡ ፈረሰኞችን ፡
በፊቱም ፡ የሚሮጡ ፡ አምሳ ፡ ሰዎች ፡ አዘጋጀ ።
፮፤ አባቱም ፡ ከቶ ፡ በሕይወቱ ፡ ሳለ ፦ እንዲህ ፡
ለምን ፡ ታደርጋለህ ? ብሎ ፡ አልተቈጣውም ፡
ነበር ፤ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ እጅግ ፡ ያማረ ፡ ሰው ፡
ነበረ ፤ ከአቤሴሎምም ፡ በኋላ ፡ ተወልዶ ፡ ነበር ።
፯፤ ሴሩውም ፡ ከጽሩያ ፡ ልጅ ፡ ከኢዮአብና ፡ ከካ
ህኑ ፡ ከአብያታር ፡ ጋር ፡ ነበረ ፥ እነርሱም ፡ አዶ
፰፤ ንያስን ፡ ተከትለው ፡ ይረዱት ፡ ነበር ። ነገር ፡
ግን ፡ ካህኑ ፡ ሳዶቅና ፡ የዮዳሄ ፡ ልጅ ፡ በናያስ ፡
ነቢዩም ፡ ናታን ፡ ሳሚም ፡ ሬሲም ፡ የዳዊትም ፡
፱፤ ኃያላን ፡ ከአዶንያስ ፡ ጋር ፡ አልነበሩም ። አዶ
ንያስም ፡ በጎችንና ፡ በሬዎችን ፡ ፍሪዳዎችንም ፡
በዓይንሮጌል ፡ አጠገብ ፡ ባለችው ፡ በዞሔሌት ፡
ድንጋይ ፡ ዘንድ ፡ ሠዋ ፤ የንጉሡንም ፡ ልጆች ፡
ወንድሞቹን ፡ ሁሉ ፥ የንጉሡንም ፡ ባሪያዎች ፥
፲፤ የይሁዳን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ጠራ ። ነገር ፡ ግን ፡
ነቢዩን ፡ ናታንን ፥ በናያስንም ፥ ኃያላኑንም ፥
ወንድሙንም ፡ ሰሎሞንን ፡ አልጠራም ።

፲፩፤ ናታንም ፡ የሰሎሞንን ፡ እናት ፡ ቤርሳቤህን ፡
እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራት ፦ ጌታችን ፡ ዳዊት ፡
ሳያውቅ ፡ የአጊት ፡ ልጅ ፡ አዶንያስ ፡ እንደ ፡
፲፪፤ ነገሠ ፡ አልሰማሽምን ? አሁንም ፡ ነዪ ፥ የል
ጅሽን ፡ የሰሎሞንን ፡ ነፍስና ፡ የአንቺን ፡ ነፍስ ፡
፲፫፤ እንድታድኚ ፡ እመክርሻለሁ ። ሂደሽ ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ግቢና ፦ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡
ሆይ ፥ ለእኔ ፡ ለባሪያህ ፦ ልጅሽ ፡ ሰሎሞን ፡
ከእኔ ፡ በኋላ ፡ ይነግሣል ፥ በዙፋኔም ፡ ይቀመ
ጣል ፡ ብለህ ፡ አልማልህልኝምን ? ስለ ፡ ምንስ ፡
፲፬፤ አዶንያስ ፡ ይነግሣል ? በዪው ። እነሆ ፥ አንቺ ፡
በዚያ ፡ ለንጉሥ ፡ ስትነግሪ ፡ እኔ ፡ ከአንቺ ፡ በኋላ ፡
እገባለሁ ፥ ቃልሽንም ፡ አጸናለሁ ።

፲፭፤ ቤርሳቤህም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ እልፍኝ ፡
ገባች ፤ ንጉሡም ፡ እጅግ ፡ ሸምግሎ ፡ ነበር ፥ ሱነ
፲፮፤ ማይቱም ፡ አቢሳ ፡ ታገለግለው ፡ ነበር ። ቤርሳ
ቤህም ፡ አጐንብሳ ፡ ለንጉሡ ፡ እጅ ፡ ነሣች ፤
፲፯፤ ንጉሡም ፦ ምን ፡ ትፈልጊያለሽ ? አለ ። እር
ስዋም ፡ አለችው ፦ ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ለባ
ሪያህ ፦ ልጅሽ ፡ ሰሎሞን ፡ ከእኔ ፡ በኋላ ፡ ይነ
ግሣል ፥ በዙፋኔም ፡ ይቀመጣል ፡ ብለህ ፡ በአ
፲፰፤ ምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ምለህልኛል ፤ አሁ
ንም ፥ እነሆ ፥ አዶንያስ ፡ መንገሡ ፡ ነው ፤ አን
ተም ፡ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ይህን ፡ አታውቅም ፤
፲፱፤ እርሱም ፡ ብዙ ፡ በሬዎችንና ፡ ፍሪዳዎችን ፡ በጎ
ችንም ፡ ሠውቶአል ፥ የንጉሡንም ፡ ልጆች ፡
ሁሉ ፥ ካህኑንም ፡ አብያታርን ፥ የሠራዊቱንም ፡
አለቃ ፡ ኢዮአብን ፡ ጠርቶአል ፤ ባሪያህን ፡ ሰሎ
፳፤ ሞንን ፡ ግን ፡ አልጠራውም ። አሁንም ፥ ጌታዬ ፡
ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ ከአንተ ፡ በኋላ ፡ በጌታዬ ፡ በን
ጉሥ ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ የሚቀመጠውን ፡ ትነግራ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ዓይን ፡ ይመ
፳፩፤ ለከትሃል ። ይህ ፡ ባይሆን ፥ ጌታዬ ፡ ከአባቶ
ችህ ፡ ጋር ፡ ባንቀላፋህ ፡ ጊዜ ፡ እኔና ፡ ልጄ ፡
ሰሎሞን ፡ እንደ ፡ ኃጢአተኞች ፡ እንቈጠራለን ።

፳፪፤ እነሆም ፥ ለንጉሡ ፡ ስትናገር ፡ ነቢዩ ፡ ናታን ፡
፳፫፤ ገባ ። ለንጉሡም ፦ እነሆ ፥ ነቢዩ ፡ ናታን ፡
መጥቶአል ፡ ብለው ፡ ነገሩት ፤ እርሱም ፡ ወደ ፡

፳፩፤ ላይ ፡ በግምባሩ ፡ ተደፋ ። አርናም ፡— ጌታዬን ፡ ንጉሡን ፡ ወደ ፡ በሪያው ፡ ያመጣው ፡ ምክንያት ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለ ። ዳዊትም ፡— መቅሠፍቱ ፡ ከሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ይከለከል ፡ ዘንድ ፡ አውድማውን ፡ ከአንተ ፡ ገዝቼ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ልሠራ ፡ ነው ፡ አለው ። ፳፪፤ አርናም ፡ ዳዊትን ፡— ጌታዬ ፡ ንጉሡ ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ ወስዶ ፡ ያቅርብ ፤ እነሆ ÷ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ በሬዎች ÷ ለሚቃጠልም ፡ እንጨት ፡ የአውድማ ፡ ዕቃና ፡ የበሬ ፡ ቀንበር ፡ አለ ። ፳፫፤ ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ ይህን ፡ ሁሉ ፡ አርና ፡ ለንጉሡ ፡ ይሰጣል ፡ አለው ፤ አርናም ፡ ንጉሡን ፡— አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቀበልህ ፡ አለው ። ፳፬፤ ንጉሡም ፡ አርናን ፡— እንዲህ ፡ አይደለም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ በዋጋ ፡ ከአንተ ፡ እገዛለሁ ፤ ለአምላኬም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ያለ ፡ ዋጋ ፡ አላቀርብም ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ አውድማውንና ፡ በሬዎቹን ፡ በአምሳ ፡ ሰቅል ፡ ብር ፡ ገዛ ። ፳፭፤ በዚያም ፡ ዳዊት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ሠራ ÷ የሚቃጠልና ፡ የደኅንነትንም ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረበ ። እግዚአብሔርም ፡ ስለ ፡ አገሪቱ ፡ የተለመነውን ፡ ሰማ ÷ መቅሠፍቱም ፡ ከእስራኤል ፡ ተከለከለ ።

# መጽሐፈ ፡ ነገሥት ፡ ቀዳማዊ ።

( እርሱም ፡ መጽሐፈ ፡ ነገሥት ፡ ሣልስ ፡ ነው ። )

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ ንጉሡ ፡ ዳዊትም ፡ ሸመገለ ፡ ዕድሜውም ፡ በዛ ፤ ልብስም ፡ ደረቡለት ÷ ነገር ፡ ግን ፡ አይሞቀውም ፡ ነበር ። ፪፤ ባሪያዎቹም ፡— ለጌታችን ፡ ለንጉሡ ፡ ድንግል ፡ ትፈለጋለች ፤ በንጉሡም ፡ ፊት ፡ ቆማ ፡ ታገልግለው ÷ በጌታችንም ፡ በንጉሡ ፡ ብብት ፡ ተኝታ ፡ ታሙቀው ፡ አሉት ። ፫፤ በእስራኤልም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ የተዋበች ፡ ቈንጆ ፡ ፈለጉ ፤ ሱነማይቱን ፡ አቢሳንም ፡ አገኙ ÷ ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ይዘዋት ፡ መጡ ። ፬፤ ቈንጆይቱም ፡ እጅግ ፡ ውብ ፡ ነበረች ፤ ንጉሡንም ፡ ትረዳውና ፡ ታገለግለው ፡ ነበር ÷ ንጉሡ ፡ ግን ፡ አያውቃትም ፡ ነበር ።

፭፤ የአጊትም ፡ ልጅ ፡ አዶንያስ ፡— ንጉሥ ፡ እሆናለሁ ፡ ብሎ ፡ ተነሣ ፤ ሰረገሎችንና ፡ ፈረሰኞችን ፡ በፊቱም ፡ የሚሮጡ ፡ አምሳ ፡ ሰዎች ፡ አዘጋጀ ። ፮፤ አባቱም ፡ ከቶ ፡ በሕይወቱ ፡ ሳለ ፡— እንዲህ ፡ ለምን ፡ ታደርጋለህ ? ብሎ ፡ አልተቈጣውም ፡ ነበር ፤ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ እጅግ ፡ ያማረ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ከአቤሴሎምም ፡ በኋላ ፡ ተወልዶ ፡ ነበር ። ፯፤ ሴሩያም ፡ ከጽሩያ ፡ ልጅ ፡ ከኢዮአብና ፡ ከካህኑ ፡ ከአብያታር ፡ ጋር ፡ ነበረ ÷ እነርሱም ፡ አዶንያስን ፡ ተከትለው ፡ ይረዱት ፡ ነበር ። ፰፤ ነገር ፡ ግን ፡ ካህኑ ፡ ሳዶቅና ፡ የዮዳሄ ፡ ልጅ ፡ በናያስ ፡ ነቢዩም ፡ ናታን ፡ ሳሚም ፡ ሬሲም ፡ የዳዊትም ፡ ኃያላን ፡ ከአዶንያስ ፡ ጋር ፡ አልነበሩም ። ፱፤ አዶንያስም ፡ በጎችንና ፡ በሬዎችን ፡ ፍሪዳዎችንም ፡ በዓይንሮጌል ፡ አጠገብ ፡ ባለችው ፡ በዞሔሌት ፡ ድንጋይ ፡ ዘንድ ፡ ሠዋ ፤ የንጉሡንም ፡ ልጆች ፡ ወንድሞቹን ፡ ሁሉ ÷ የንጉሡንም ፡ ባሪያዎች ÷ ፲፤ የይሁዳን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ጠራ ። ነገር ፡ ግን ፡ ነቢዩን ፡ ናታንን ÷ በናያስንም ÷ ኃያላኑንም ÷ ወንድሙንም ፡ ሰሎሞንን ፡ አልጠራም ።

፲፩፤ ናታንም ፡ የሰሎሞንን ፡ እናት ፡ ቤርሳቤህን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራት ፡— ጌታችን ፡ ዳዊት ፡ ሳያውቅ ፡ የአጊት ፡ ልጅ ፡ አዶንያስ ፡ እንደ ፡ ነገሠ ፡ አልሰማሽምን ? ፲፪፤ አሁንም ፡ ነዪ ÷ የልጅሽን ፡ የሰሎሞንን ፡ ነፍስና ፡ የአንቺን ፡ ነፍስ ፡ እንድታድኚ ፡ እመክርሻለሁ ። ፲፫፤ ሄደሽ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ግቢና ፡— ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ ለእኔ ፡ ለባሪያህ ፡— ልጅሽ ፡ ሰሎሞን ፡ ከእኔ ፡ በኋላ ፡ ይነግሣል ÷ በዙፋኔም ፡ ይቀመጣል ፡ ብለህ ፡ አልማልህልኝምን ? ስለ ፡ ምንስ ፡ አዶንያስ ፡ ይነግሣል ? በዪው ። ፲፬፤ እነሆ ÷ አንቺ ፡ በዚያ ፡ ለንጉሥ ፡ ስትነግሪ ፡ እኔ ፡ ከአንቺ ፡ በኋላ ፡ እገባለሁ ÷ ቃልሽንም ፡ አጸናለሁ ።

፲፭፤ ቤርሳቤህም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ እልፍኝ ፡ ገባች ፤ ንጉሡም ፡ እጅግ ፡ ሸምግሎ ፡ ነበር ÷ ሱነማይቱም ፡ አቢሳ ፡ ታገለግለው ፡ ነበር ። ፲፮፤ ቤርሳቤህም ፡ አጐንብሳ ፡ ለንጉሡ ፡ እጅ ፡ ነሣች ፤ ንጉሡም ፡— ምን ፡ ትፈልጊያለሽ ? አለ ። ፲፯፤ እርስዋም ፡ አለችው ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ÷ አንተ ፡ ለባሪያህ ፡— ልጅሽ ፡ ሰሎሞን ፡ ከእኔ ፡ በኋላ ፡ ይነግሣል ÷ በዙፋኔም ፡ ይቀመጣል ፡ ብለህ ፡ በአምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ምለህልኛል ፤ ፲፰፤ አሁንም ÷ እነሆ ÷ አዶንያስ ፡ መንገሡ ፡ ነው ፤ አንተም ፡ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ይህን ፡ አታውቅም ፤ ፲፱፤ እርሱም ፡ ብዙ ፡ በሬዎችንና ፡ ፍሪዳዎችን ፡ በጎችንም ፡ ሠውቶአል ÷ የንጉሡንም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ÷ ካህኑንም ፡ አብያታርን ÷ የሠራዊቱንም ፡ አለቃ ፡ ኢዮአብን ፡ ጠርቶአል ፤ ባሪያህን ፡ ሰሎሞንን ፡ ግን ፡ አልጠራውም ። ፳፤ አሁንም ÷ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ ከአንተ ፡ በኋላ ፡ በጌታዬ ፡ በንጉሥ ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ የሚቀመጠውን ፡ ትነግራቸው ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ዓይን ፡ ይመለከትሃል ። ፳፩፤ ይህ ፡ ባይሆን ÷ ጌታዬ ፡ ከአባቶችህ ፡ ጋር ፡ በንቀላፋህ ፡ ጊዜ ፡ እኔና ፡ ልጄ ፡ ሰሎሞን ፡ እንደ ፡ ኃጢአተኞች ፡ እንቈጠራለን ።

፳፪፤ እነሆም ÷ ለንጉሡ ፡ ስትናገር ፡ ነቢዩ ፡ ናታን ፡ ገባ ። ፳፫፤ ለንጉሡም ፡— እነሆ ÷ ነቢዩ ፡ ናታን ፡ መጥቶአል ፡ ብለው ፡ ነገሩት ፤ እርሱም ፡ ወደ ፡

ንጉሡ ፡ ፊት ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ በግምባሩ ፡ በም
ድር ፡ ላይ ፡ ተደፍቶ ፡ ለንጉሡ ፡ እጅ ፡ ነሣ ።
፳፬ ናታንም ፡ አለ ፡— ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ÷
አንተ ፡— ከእኔ ፡ በኋላ ፡ አዶንያስ ፡ ይነግሣል ÷
፳፭ በዙፋኔም ፡ ላይ ፡ ይቀመጣል ፡ ብለሃልን ? እርሱ ፡
ዛሬ ፡ ወርዶ ፡ ብዙ ፡ በሬዎችንና ፡ ፍሪዳዎችን ፡
በጎችንም ፡ ሠውቶአል ÷ የንጉሡንም ፡ ልጆች ፡
ሁሉ ÷ የሠራዊትንም ፡ አለቃ ፡ ኢዮአብን ÷
ካህኑንም ፡ አብያታርን ፡ ጠርቶአል ፤ እነሆም ÷
በፊቱ ፡ እየበሉና ፡ እየጠጡ ፡— አዶንያስ ፡ ሺህ ፡
፳፮ ዓመት ፡ ይንገሥ ፡ ይላሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ እኔን ፡
ባሪያህን ÷ ካህኑንም ፡ ሳዶቅን ÷ የዮዳሄንም ፡
ልጅ ፡ በናያስን ÷ ባሪያህንም ፡ ሰሎሞንን ፡ አል
፳፯ ጠራም ። በውኑ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ከጌታዬ ፡ ከን
ጉሡ ፡ የተደረገ ፡ ነውን ? ለባሪያህም ፡ ከአንተ ፡
በኋላ ፡ በጌታዬ ፡ በንጉሡ ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ የሚ
ቀመጠውን ፡ አልነገርህምን ?

፳፰ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡— ቤርሳቤህን ፡ ጥሩልኝ ፡
ብሎ ፡ መለሰ ። ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ገባች ÷ በን
፳፱ ጉሡም ፡ ፊት ፡ ቆመች ። ንጉሡም ፡— ነፍሴን ፡
ከመከራ ፡ ሁሉ ፡ ያዳነኝ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔ
፴ ርን ፤ በእውነት ፡— ልጅሽ ፡ ሰሎሞን ፡ ከእኔ ፡
በኋላ ፡ ይነግሣል ÷ በእኔም ፡ ፋንታ ፡ በዙፋኔ ፡
ላይ ፡ ይቀመጣል ፡ ብዬ ፡ በእስራኤል ፡ አምላክ ፡
በእግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ማልሁልሽ ÷ እንዲሁ ፡
ዛሬ ፡ በእውነት ፡ አደርጋለሁ ፡ ብሎ ፡ ማለ ።
፴፩ ቤርሳቤህም ፡ በግምባርዋ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ተደ
ፍታ ፡ ለንጉሡ ፡ እጅ ፡ ነሣችና ፡— ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡
ዳዊት ፡ ለዘላለም ፡ በሕይወት ፡ ይኑር ፡ አለች ።

፴፪ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡— ካህኑን ፡ ሳዶቅንና ፡ ነቢ
ዩን ፡ ናታንን ፡ የዮዳሄንም ፡ ልጅ ፡ በናያስን ፡
ጥሩልኝ ፡ አለ ። ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ፊት ፡ ገቡ ።
፴፫ ንጉሡም ፡ አላቸው ፡— የጌታችሁን ፡ ባሪያዎች ፡
ይዛችሁ ፡ ሂዱ ÷ ልጄንም ፡ ሰሎሞንን ፡ በበቅ
ሎዬ ፡ ላይ ፡ አስቀምጡት ÷ ወደ ፡ ግዮንም ፡ አው
፴፬ ርዱት ፤ በዚያም ፡ ካህኑ ፡ ሳዶቅና ፡ ነቢዩ ፡ ናታን ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ አድርገው ፡ ይቀ
ቡት ፤ ቀንደ ፡ መለከትም ፡ ነፍታችሁ ፡— ሰሎ
፴፭ ሞን ፡ ሺህ ፡ ዓመት ፡ ይንገሥ ፡ በሉ ። በኋላ
ውም ፡ ተከትላችሁ ፡ ውጡ ፤ እርሱም ፡ መጥቶ ፡
በዙፋኔ ፡ ላይ ፡ ይቀመጥ ÷ በእኔም ፡ ፋንታ ፡
ይንገሥ ፤ በእስራኤልና ፡ በይሁዳም ፡ ላይ ፡
፴፮ አለቃ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ አዝዣለሁ ። የዮዳሄም ፡
ልጅ ፡ በናያስ ፡ መልሶ ፡ ለንጉሡ ፡ አለ ፡— ያበጅ ፡
ያድርግ ፤ የጌታዬም ፡ የንጉሥ ፡ አምላክ ፡ ይህን ፡
፴፯ ይናገር ። እግዚአብሔር ፡ ከጌታዬ ፡ ከንጉሥ ፡
ጋር ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ እንዲሁ ፡ ከሰሎሞን ፡ ጋር ፡
ይሁን ÷ ዙፋኑንም ፡ ከጌታዬ ፡ ከንጉሡ ፡ ዳዊት ፡
ዙፋን ፡ የበለጠ ፡ ያድርግ ።

፴፰ ካህኑም ፡ ሳዶቅና ፡ ነቢዩ ፡ ናታን ፡ የዮዳሄም ፡
ልጅ ፡ በናያስ ፡ ከሊታውያንና ፡ ፈሊታውያንም ፡
ወረዱ ÷ ሰሎሞንንም ፡ በንጉሡ ፡ በዳዊት ፡
በቅሎ ፡ ላይ ፡ አስቀምጠው ፡ ወደ ፡ ግዮን ፡ አመ
፴፱ ጡት ። ካህኑም ፡ ሳዶቅ ፡ ከድንኳኑ ፡ የቅብዓ
ቱን ፡ ቀንድ ፡ ወስዶ ፡ ሰሎሞንን ፡ ቀባ ፤ ቀንደ ፡
መለከትም ፡ ነፉ ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡— ሰሎሞን ፡
፵ ሺህ ፡ ዓመት ፡ ይንገሥ ፡ አሉ ። ሕዝቡም ፡
ሁሉ ፡ እርሱን ፡ ተከትለው ፡ ወጡ ÷ ሕዝቡም ፡
ዘፈን ፡ ይዘፍኑ ፡ ነበር ÷ በታላቅም ፡ ደስታ ፡
ደስ ፡ አላቸው ፤ ከጩኸታቸውም ፡ የተነሣ ፡
ምድር ፡ ተናወጠች ።

፵፩ አዶንያስና ፡ እርሱም ፡ የጠራቸው ፡ ሁሉ ፡
መብሉና ፡ መጠጡ ፡ ተፈጸሞ ፡ ሳለ ፡ ሰሙ ፤
ኢዮአብም ፡ የቀንደ ፡ መለከት ፡ ድምፅ ፡ በሰማ ፡
ጊዜ ፡— ይህ ፡ በከተማ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ የሽብር ፡
፵፪ ድምፅ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለ ። እርሱም ፡ ይህን ፡
ሲናገር ፡ የካህኑ ፡ የአብያታር ፡ ልጅ ፡ ዮናታን ፡
መጣ ፤ አዶንያስም ፡— አንተ ፡ መልካም ፡ ሰው ፡
ነህና ÷ መልካም ፡ ታወራልናለህና ፡ ግባ ፡ አለው ።
፵፫ ዮናታንም ፡ ለአዶንያስ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ መለሰ ፡—
በእውነት ፡ ጌታችን ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ሰሎሞ
፵፬ ንን ፡ አነገሠው ። ንጉሡም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
ካህኑን ፡ ሳዶቅንና ፡ ነቢዩን ፡ ናታንን ፡ የዮዳሄ
ንም ፡ ልጅ ፡ በናያስን ፡ ከሊታውያንንና ፡ ፈሊ
ታውያንንም ፡ ሰደደ ÷ በንጉሡም ፡ በቅሎ ፡ ላይ ፡
፵፭ አስቀመጡት ። ካህኑም ፡ ሳዶቅና ፡ ነቢዩ ፡ ናታን ፡
በግዮን ፡ ንጉሥ ፡ አድርገው ፡ ቀቡት ፤ ከዚ
ያም ፡ ደስ ፡ ብሎአቸው ፡ ወጡ ÷ ከተማይቱም ፡
አስተጋባች ፤ የሰማችሁትም ፡ ድምፅ ፡ ይህ ፡
፵፮ ነው ። ደግሞም ፡ ሰሎሞን ፡ በመንግሥቱ ፡
፵፯ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ተቀምጦአል ። የንጉሡም ፡ ባሪ
ያዎች ፡ ገብተው ፡— እግዚአብሔር ፡ የሰሎሞ
ንን ፡ ስም ፡ ከስምህ ፡ ዙፋኑንም ፡ ከዙፋንህ ፡ የበ
ለጠ ፡ ያድርግ ፡ ብለው ፡ ጌታችንን ፡ ንጉሡን ፡
ዳዊትን ፡ ባረኩ ፤ ንጉሡም ፡ በአልጋው ፡ ላይ ፡
፵፰ ሆኖ ፡ ሰገደ ። ንጉሡም ፡ ደግሞ ፡— ዓይኔ ፡
እያየ ፡ ዛሬ ፡ በዙፋኔ ፡ ላይ ፡ የሚቀመጠውን ፡
የሰጠኝ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡
ይመስገን ፡ አለ ።

፵፱ አዶንያስም ፡ የጠራቸው ፡ ሁሉ ፡ ፈሩ ÷ ተነ
ሥተውም ፡ እያንዳንዳቸው ፡ በየመንገዳቸው ፡
፶ ሄዱ ። አዶንያስም ፡ ሰሎሞንን ፡ ፈራ ÷ ተነሥ
ቶም ፡ ሄደ ÷ የመሠዊያውንም ፡ ቀንድ ፡ ያዘ ።
፶፩ ለሰሎሞንም ፡— እነሆ ÷ አዶንያስ ፡ ንጉሡን ፡ ሰሎ
ሞንን ፡ ፈርቶ ፡— ንጉሡ ፡ ሰሎሞን ፡ ባሪያውን ፡
በሰይፍ ፡ እንዳይገድለኝ ፡ ዛሬ ፡ ይማልልኝ ፡
ብሎ ፡ የመሠዊያውን ፡ ቀንድ ፡ ይዞአል ፡ አሉት ።
፶፪ ሰሎሞንም ፡— እርሱ ፡ አካሄዱን ፡ ያሳመረ ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ ከእርሱ ፡ አንዲት ፡ ጠጕር ፡ እንኳ ፡
በምድር ፡ ላይ ፡ አትወድቅም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ክፋት ፡
የተገኘበት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይሞታል ፡ አለ ።
፶፫ ንጉሡ ፡ ሰሎሞንም ፡ ላከ ÷ ከመሠዊያውም ፡ አወ
ረዱት ፤ መጥቶም ፡ ለንጉሡ ፡ ለሰሎሞን ፡ እጅ ፡
ነሣ ÷ ሰሎሞንም ፡— ወደ ፡ ቤትህ ፡ ሂድ ፡ አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ዳዊትም ፡ የሚሞትበት ፡ ቀን ፡ ቀረበ ፤ ልጁ
ንም ፡ ሰሎሞንን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ አዘዘው ፡—
፪ እኔ ፡ የምድሩን ፡ ሁሉ ፡ መንገድ ፡ እሄዳለሁ ፤
፫ በርታ ፡ ሰውም ፡ ሁን ፤ የምታደርገውንና ፡ የም
ትሄድበትን ፡ ሁሉ ፡ ታከናውን ፡ ዘንድ ፥ በሙሴ ፡
ሕግ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ሥርዓቱንና ፡ ትእዛዛቱን ፡
ፍርዱንና ፡ ምስክሩንም ፡ ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፥
በመንገዱም ፡ ትሄድ ፡ ዘንድ ፥ የአምላክህን ፡ የእ
፬ ግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ጠብቅ ። ይኸውም ፡
ደግሞ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ እኔ ፡— ልጆችህ ፡
መንገዳቸውን ፡ ቢጠብቁ ፥ በፊቴም ፡ በፍጹም ፡
ልባቸውና ፡ በፍጹም ፡ ነፍሳቸው ፡ በእውነት ፡
ቢሄዱ ፡ ከእስራኤል ፡ ዙፋን ፡ ሰው ፡ አይቈረጥ
ብህም ፡ ብሎ ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ ያጸና ፡
፭ ዘንድ ፡ ነው ። አንተም ፡ ደግሞ ፡ የጽሩያ ፡ ልጅ ፡
ኢዮአብ ፥ ሁለቱን ፡ የእስራኤልን ፡ ጭፍራ ፡
አለቆች ፡ የኔር ፡ ልጅ ፡ አበኔርን ፡ የዩቴሩንም ፡
ልጅ ፡ አሜሳይን ፡ ገድሎ ፥ በእኔ ፡ ላይ ፡ ያደረ
ገውን ፡ ታውቃለህ ፤ የሰልፉንም ፡ ደም ፡ በሰ
ላም ፡ አፈሰሰ ፥ በወገቡም ፡ ባለው ፡ ድግና ፡
በእግሩ ፡ ባለው ፡ ጫማ ፡ ንጹሕ ፡ ደም ፡ አኖረ ።
፮ አንተም ፡ እንደ ፡ ጥበብህ ፡ አድርግ ፥ ሽበቱንም ፡
፯ በሰላም ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ አታውርደው ። ከወ
ንድምህ ፡ ከአቤሴሎም ፡ ፊት ፡ በሸሸሁ ፡ ጊዜ ፡
ቀርበውኛልና ፡ ለገለዓዳዊው ፡ ለቤርዜሊ ፡
ልጆች ፡ መልካም ፡ ቸርነት ፡ አድርግላቸው ፥
በማዕድህም ፡ ከሚበሉት ፡ መካከል ፡ ይሁኑ ።
፰ እኔም ፡ ወደ ፡ መሃናይም ፡ በሄድሁ ፡ ጊዜ ፡
ብርቱ ፡ እርግማን ፡ የረገመኝ ፡ የብራቂም ፡ አገር ፡
ሰው ፡ የብንያማዊው ፡ የጌራ ፡ ልጅ ፡ ሳሚ ፥
እነሆ ፥ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ ዮር
ዳኖስን ፡ በተሻገርሁ ፡ ጊዜ ፡ ሊቀበለኝ ፡ ወረደ ፥
እኔም ፡— በሰይፍ ፡ አልገድልህም ፡ ብዬ ፡ በእ
፱ ግዚአብሔር ፡ ምዬለታለሁ ። አንተ ፡ ግን ፡ ጥበ
በኛ ፡ ሰው ፡ ነህና ፡ ያለ ፡ ቅጣት ፡ አትተወው ፤
የምታደርግበትንም ፡ አንተ ፡ ታውቃለህ ፥ ሽበ
ቱንም ፡ ከደም ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ አው
ርድ ።
፲ ዳዊትም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በዳ
፲፩ ዊትም ፡ ከተማ ፡ ተቀበረ ። ዳዊትም ፡ በእስራ
ኤል ፡ ላይ ፡ የነገሠው ፡ ዘመን ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡
ነበረ ። በኬብሮን ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ በኢ
የሩሳሌምም ፡ ሠላሳ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ።
፲፪ ሰሎሞንም ፡ በአባቱ ፡ በዳዊት ፡ ዙፋን ፡ ተቀ
መጠ ፤ መንግሥቱም ፡ እጅግ ፡ ጸና ።
፲፫ የአጊት ፡ ልጅ ፡ አዶንያስም ፡ ወደ ፡ ሰሎሞን ፡
እናት ፡ ወደ ፡ ቤርሳቤህ ፡ መጣ ፤ እርስዋም ፡—
ወደ ፡ እኔ ፡ መምጣትህ ፡ በሰላም ፡ ነውን ? አለች ፤
፲፬ እርሱም ፡— በሰላም ፡ ነው ፡ አለ ። ደግሞም ፡—
ከአንቺ ፡ ጋር ፡ጉዳይ ፡ አለኝ ፡ አለ ፤ እርስዋም ፡—
፲፭ ተናገር ፡ አለች ። እርሱም ፡— መንግሥቱ ፡
ለእኔ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፥ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡
ንጉሥ ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ ፊታቸውን ፡ ወደ ፡
እኔ ፡ አድርገው ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ አንቺ ፡ ታውቂ
ያለሽ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
ሆኖለታልና ፡ መንግሥቱ ፡ ከእኔ ፡ አልፎ ፡ ለወ
፲፮ ንድሜ ፡ ሆኖአል ። አሁንም ፡ አንዲት ፡ ልመና ፡
እለምንሻለሁ ፤ አታሳፍሪኝ ፡ አለ ። እርስዋም ፡—
፲፯ ተናገር ፡ አለችው ። እርሱም ፡— አያሳፍርሽ
ምና ፡ ሱነማይቱን ፡ አቢሳን ፡ ይድርልኝ ፡ ዘንድ ፡
ለንጉሡ ፡ ለሰሎሞን ፡ እንድትነግሪው ፡ እለም
፲፰ ንሻለሁ ፡ አለ ። ቤርሳቤህም ፡— መልካም ፡ ነው ፥
ስለ ፡ አንተ ፡ ለንጉሡ ፡ እነግረዋለሁ ፡ አለች ።
፲፱ ቤርሳቤህም ፡ የአዶንያስን ፡ ነገር ፡ ትነግረው ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ሰሎሞን ፡ ገባች ፤
ንጉሡም ፡ ሊቀበላት ፡ ተነሣ ፡ ሰግዶላትም ፥ በዙ
ፋኑም ፡ ተቀመጠ ፤ ለንጉሡም ፡ እናት ፡ ወን
በር ፡ አስመጣላት ፥ በቀኙም ፡ ተቀመጠች ።
፳ እርስዋም ፡— አንዲት ፡ ታናሽ ፡ ልመና ፡ እለም
ንሃለሁ ፤ አታሳፍረኝ ፡ አለች ። ንጉሡም ፡—
እናቴ ፡ ሆይ ፥ አላሳፍርሽምና ፡ ለምኚ ፡ አላት ።
፳፩ እርስዋም ፡— ሱነማይቱ ፡ አቢሳ ፡ ለወንድምህ ፡
፳፪ ለአዶንያስ ፡ ትዳርለት ፡ አለች ። ንጉሡም ፡
ሰሎሞን ፡ ለእናቱ ፡ መለሰ ፡— ሱነማይቱን ፡
አቢሳን ፡ ለአዶንያስ ፡ ለምን ፡ ትለምኚለታለሽ ?
ታላቅ ፡ ወንድሜ ፡ ነውና ፡ መንግሥትን ፡ ደግሞ ፡
ለምኚለት ፤ ካህኑም ፡ አብያታርና ፡ የጽሩያ ፡
ልጅ ፡ ኢዮአብ ፡ ደግሞ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ናቸው ፡
፳፫ አላት ። ንጉሡም ፡ ሰሎሞን ፡— አዶንያስ ፡ ይህን ፡
ቃል ፡ በሕይወቱ ፡ ላይ ፡ አለመናገሩ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ያድርግብኝ ፥ ይህንም ፡
፳፬ ይጨምርብኝ ። አሁንም ፡ ያጸናኝ ፥ በአባቴም ፡
በዳዊት ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ያስቀመጠኝ ፥ እንደ ፡
ተናገረውም ፡ ቤትን ፡ የሠራልኝ ፡ ሕያው ፡ እግ
ዚአብሔርን ፤ ዛሬ ፡ አዶንያስ ፡ ፈጽሞ ፡ ይገደ
፳፭ ላል ፡ ብሎ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ማለ ። ንጉሡም ፡
ሰሎሞን ፡ የዮዳሄን ፡ ልጅ ፡ በናያስን ፡ ላከ ፤ እር
ሱም ፡ ወደቀበት ፥ ሞተም ።
፳፮ ንጉሡም ፡ ካህኑን ፡ አብያታርን ፡— አንተ ፡
ዛሬ ፡ የሞት ፡ ሰው ፡ ነበርህ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የአም
ላክን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ በአባቴ ፡ በዳ
ዊት ፡ ፊት ፡ ስለ ፡ ተሸከምህ ፥ አባቴም ፡ የተቀ
በለውን ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ስለ ፡ ተቀበልህ ፡
አልገድልህምና ፡ በዓናቶት ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡
፳፯ እርሻህ ፡ ሂድ ፡ አለው ። በሴሎም ፡ በዔሊ ፡
ቤት ፡ ላይ ፡ የተናገረው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡
ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ ሰሎሞን ፡ አብያታርን ፡ ከእግ
ዚአብሔር ፡ ክህነት ፡ አወጣው ።
፳፰ ለኢዮአብም ፡ ወሬ ፡ ደረሰለት ፤ ኢዮአብም ፡
አቤሴሎምን ፡ አልተከተለም ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ አዶ
ንያስን ፡ ተከትሎ ፡ ነበር ። ኢዮአብም ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ድንኳን ፡ ሸሽቶ ፡ የመሠዊያ
፳፱ ውን ፡ ቀንድ ፡ ያዘ ። ንጉሡም ፡ ሰሎሞን ፡ ኢዮ
አብ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ድንኳን ፡ ሸሽቶ ፡
መሠዊያውን ፡ እንደ ፡ ያዘ ፡ ሰማ ፤ ሰሎሞንም ፡
የዮዳሄን ፡ ልጅ ፡ በናያስን ፡— ሂድ ፡ ውደቅበት ፡

፴፤ ብሎ ፡ አዘዘው ። በናያስም ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ድንኳን ፡ መጥቶ ፡— ንጉሡ ፡— ውጣ ፡
ይልሃል ፡ አለው ፤ እርሱም ፡— በዚህ ፡ እሞታ
ለሁ ፡ እንጂ ፡ አልወጣም ፡ አለ ። በናያስም ፡—
ኢዮአብ ፡ የተናገረው ፡ ቃል ፡ የመለሰልኝም ፡
እንዲህ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወሬ ፡
፴፩ አመጣ ። ንጉሡም ፡ አለው ፡— እንደ ፡ ነገረህ ፡
አድርግ ፤ ኢዮአብም ፡ በከንቱ ፡ ያፈሰሰውን ፡
ደም ፡ ከእኔና ፡ ከአባቴ ፡ ቤት ፡ ታርቅ ፡ ዘንድ ፡
፴፪ ገድለህ ፡ ቅበረው ። አባቴ ፡ ዳዊት ፡ ሳያውቅ ፡
ከእርሱ ፡ የሚሻሉትን ፡ ሁለቱን ፡ ጻድቃን ፡
ሰዎች ፥ የእስራኤልን ፡ ሠራዊት ፡ አለቃ ፡ የኔ
ርን ፡ ልጅ ፡ አበኔርን ፥ የይሁዳንም ፡ ሠራዊት ፡
አለቃ ፡ የዬቴርን ፡ ልጅ ፡ አሜሳይን ፥ በሰይፍ ፡
ገድሎአልና ፡ እግዚአብሔር ፡ ደሙን ፡ በራሱ ፡
፴፫ ላይ ፡ ይመልሰው ። ደማቸውም ፡ በኢዮአብ ፡
ራስና ፡ በዘሩ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ለዘላለም ፡ ይመለስ ፤
ለዳዊት ፡ ግን ፡ ለዘሩና ፡ ለቤቱ ፡ ለዙፋኑም ፡
የእግዚአብሔር ፡ ሰላም ፡ ለዘላለም ፡ ይሁን ።
፴፬ የዮዳሄም ፡ ልጅ ፡ በናያስ ፡ ወጥቶ ፡ ወደቀበት ፡
ገደለውም ፤ በምድረ ፡ በዳም ፡ ባለው ፡ በቤቱ ፡
፴፭ ተቀበረ ። ንጉሡም ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ የዮዳ
ሄን ፡ ልጅ ፡ በናያስን ፡ የሠራዊቱ ፡ አለቃ ፡
አደረገ ፤ በአብያታርም ፡ ፋንታ ፡ ካህኑን ፡ ሳዶ
ቅን ፡ አደረገ ።

፴፮ ንጉሡም ፡ ልኮ ፡ ሳሚን ፡ አስጠራውና ፡—
በኢየሩሳሌም ፡ ቤት ፡ ሠርተህ ፡ ተቀመጥ ፥
፴፯ ወዲህና ፡ ወዲያም ፡ አትውጣ ። በወጣህበትም ፡
ቀን ፥ የቄድሮንንም ፡ ፈፋ ፡ በተሻገርህበት ፡
ቀን ፡ ፈጽመህ ፡ እንድትሞት ፡ እወቅ ፤ ደምህ ፡
፴፰ በራስህ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፡ አለው ። ሳሚም ፡
ንጉሡን ፡— ነገሩ ፡ መልካም ፡ ነው ፤ ጌታዬ ፡
ንጉሥ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ባሪያህ ፡ እንዲሁ ፡
ያደርጋል ፡ አለው ፤ ሳሚም ፡ በኢየሩሳሌም ፡
ብዙ ፡ ቀን ፡ ተቀመጠ ።

፴፱ ከሦስት ፡ ዓመትም ፡ በኋላ ፡ ከሳሚ ፡ ባሪያዎች ፡
ሁለቱ ፡ ወደ ፡ ጌት ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ መዓካ ፡
ልጅ ፡ ወደ ፡ አንኩስ ፡ ኰበለሉ ፤ ሳሚንም ፡—
እነሆ ፥ ባሪያዎችህ ፡ በጌት ፡ ናቸው ፡ ብለው ፡
፵ ነገሩት ። ሳሚም ፡ ተነሣ ፥ አህያውንም ፡ ጭኖ ፡
ባሪያዎቹን ፡ ይሻ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ጌት ፡ ወደ ፡
አንኩስ ፡ ዘንድ ፡ ሄደ ፤ ሳሚም ፡ ሄዶ ፡ ባሪያዎ
፵፩ ቹን ፡ ከጌት ፡ አመጣ ። ሰሎሞንም ፡ ሳሚ ፡ ከኢ
የሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ጌት ፡ ሄዶ ፡ እንደ ፡ ተመለሰ ፡
፵፪ ሰማ ። ንጉሡም ፡ ልኮ ፡ ሳሚን ፡ አስጠራና ፡—
ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ ለመሄድ ፡ በወጣህ ፡ ቀን ፡
ፈጽመህ ፡ እንድትሞት ፡ እወቅ ፡ ብዬ ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ አላስማልሁህምን ? ወይስ ፡ አላስመ
ሰከርሁብህምን ? አንተም ፡— ቃሉ ፡ መልካም ፡
፵፫ ነው ፥ ሰምቻለሁ ፡ አልኸኝ ። የእግዚአብሔርን ፡
መሐላ ፡ እኔስ ፡ ያዘዝሁህን ፡ ትእዛዝ ፡ ስለ ፡
፵፬ ምን ፡ አልጠበቅህም ? አለው ። ንጉሡም ፡
ደግሞ ፡ ሳሚን ፡— አንተ ፡ በአባቴ ፡ በዳዊት ፡
ላይ ፡ የሠራኸውን ፡ ልብህም ፡ ያሰበውን ፡ ክፋት ፡
ሁሉ ፡ ታውቃለህ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ክፋት
ህን ፡ በራስህ ፡ ላይ ፡ ይመልሳል ። ፵፭ ንጉሡ ፡
ሰሎሞን ፡ ግን ፡ የተባረከ ፡ ይሆናል ፥ የዳዊትም ፡
ዙፋን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለዘላለም ፡ ይጸ
ናል ፡ አለው ። ፵፮ ንጉሡም ፡ የዮዳሄን ፡ ልጅ ፡
በናያስን ፡ አዘዘው ፥ ወጥቶም ፡ ወደቀበት ፥
ሞተም ። መንግሥትም ፡ በሰሎሞን ፡ እጅ ፡
ጸና ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ሰሎሞንም ፡ ለግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ለፈርዖን ፡
አማች ፡ ሆነ ፤ የፈርዖንን ፡ ልጅ ፡ አገባ ፥ ቤቱ
ንና ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ በኢየሩሳሌ
ምም ፡ ዙሪያ ፡ ያለውን ፡ ቅጥር ፡ ሠርቶ ፡ እስኪ
ፈጽም ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ከተማ ፡ አመ
ጣት ። ፪ እስከዚያም ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ ስም ፡ መቅደስ ፡ አልተሠራም ፡ ነበርና ፡
ሕዝቡ ፡ በኮረብታ ፡ ላይ ፡ ባሉት ፡ መስገጃዎች ፡
ይሠዋ ፡ ነበር ። ፫ ሰሎሞንም ፡ እግዚአብሔርን ፡
ይወድድ ፡ ነበር ፥ በአባቱም ፡ በዳዊት ፡ ሥር
ዓት ፡ ይሄድ ፡ ነበር ፤ ብቻ ፡ በኮረብታ ፡ መስገጃ ፡
ይሠዋና ፡ ያጥን ፡ ነበር ።

፬ ገባዖን ፡ ዋና ፡ የኮረብታ ፡ መስገጃ ፡ ነበረችና ፡
ንጉሡ ፡ ይሠዋ ፡ ዘንድ ፡ ወደዚያ ፡ ሄደ ፤ ሰሎ
ሞንም ፡ በዚያ ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡
የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረበ ። ፭ እግዚአ
ብሔርም ፡ በገባዖን ፡ ለሰሎሞን ፡ በሌሊት ፡ በሕ
ልም ፡ ተገለጠለት ፤ እግዚአብሔርም ፡— ምን ፡
እንድሰጥህ ፡ ለምን ፡ አለ ። ፮ ሰሎሞንም ፡ አለ ፡—
እርሱ ፡ በፊትህ ፡ በእውነትና ፡ በጽድቅ ፡ በል
ብም ፡ ቅንነት ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ሄደ ፥
ከባሪያህ ፡ ከአባቴ ፡ ከዳዊት ፡ ጋር ፡ ታላቅ ፡ ቸር
ነት ፡ አድርገሃል ፤ ዛሬ ፡ እንደ ፡ ሆነም ፡ በዙ
ፋኑ ፡ ላይ ፡ የሚቀመጥ ፡ ልጅ ፡ ሰጥተህ ፡ ታላ
ቁን ፡ ቸርነትህን ፡ አቆይተህለታል ። ፯ አሁንም ፥
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፥ እኔን ፡ ባሪያህን ፡ በአ
ባቴ ፡ በዳዊት ፡ ፋንታ ፡ አንግሠኸኛል ፤ እኔም ፡
መውጫዬንና ፡ መግቢያን ፡ የማላውቅ ፡ ታናሽ ፡
ብላቴና ፡ ነኝ ። ፰ ባሪያህም ፡ ያለው ፡ አንተ ፡ በመ
ረጥኸው ፡ ሕዝብህ ፡ ስለ ፡ ብዛቱም ፡ ይቈጠርና ፡
ይመጠን ፡ ዘንድ ፡ በማይቻል ፡ በታላቅ ፡ ሕዝብ ፡
መካከል ፡ ነው ። ፱ ስለዚህም ፡ በሕዝብህ ፡ ላይ ፡
መፍረድ ፡ ይችል ፡ ዘንድ ፥ መልካሙንና ፡ ክፉ
ውንም ፡ ይለይ ፡ ዘንድ ፡ ለባሪያህ ፡ አስተዋይ ፡
ልቡና ፡ ስጠው ፤ አለዚያማ ፡ በዚህ ፡ በታላቅ ፡
ሕዝብህ ፡ ላይ ፡ ይፈርድ ፡ ዘንድ ፡ ማን ፡ ይችላል ?

፲ ሰሎሞንም ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ስለ ፡ ለመነ ፥ ነገሩ ፡
እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ አሰኘው ። ፲፩ እግዚአብ
ሔርም ፡ አለው ፡— ፍርድን ፡ ትለይ ፡ ዘንድ ፡
ለራስህ ፡ ማስተዋልን ፡ ለመንህ ፡ እንጂ ፡ ለራ
ስህ ፡ ብዙ ፡ ዘመናትን ፡ ባለጠግነትንም ፡ የጠላቶ
ችህንም ፡ ነፍስ ፡ ሳትለምን ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ለም
ነሃልና ፡ ፲፪ እነሆ ፥ እኔ ፡ እንደ ፡ ቃልህ ፡ አድርጌ
ልሃለሁ ፤ እነሆ ፥ ማንም ፡ የሚመስልህ ፡ ከአ

ንተ ፡ በፊት ፡ እንደሌለ ፡ ከአንተም ፡ በኋላ ፡
እንዳይነሣ ፡ አድርጌ ፡ ጥበበኛና ፡ አስተዋይ ፡
፲፫ ልቡና ፡ ሰጥቼሃለሁ ። ደግሞም ፡ ከነገሥታት ፡
የሚመስልህ ፡ ማንም ፡ እንዳይኖር ፡ ያልለመን
ኸውን ፡ ባለጠግነትና ፡ ክብር ፡ ሰጥቼሃለሁ ።
፲፬ አባትህም ፡ ዳዊት ፡ እንደ ፡ ሄደ ፥ ሥርዓቴንና ፡
ትእዛዜን ፡ ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ በመንገዴ ፡ የሄ
ድህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ዕድሜህን ፡ አረዝመዋለሁ ።
፲፭ ሰሎሞንም ፡ ነቃ ፥ እነሆም ፥ ሕልም ፡ ነበረ ፤
ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ መጥቶ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ ቆመ ፥ የሚ
ቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ አሳረገ ፥ የደኅንነ
ትንም ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረበ ፥ ለባሪያዎቹም ፡
ሁሉ ፡ ግብዣ ፡ አደረገ ።

፲፮ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሁለት ፡ ጋለሞቶች ፡ ሴቶች ፡
፲፯ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ መጥተው ፡ በፊቱ ፡ ቆሙ ። አንደ
ኛይቱም ፡ ሴት ፡ አለች ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ እኔና ፡
ይህች ፡ ሴት ፡ በአንድ ፡ ቤት ፡ እንኖራለን ፤
እኔም ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ በቤት ፡ ሳለሁ ፡ ወለ
፲፰ ድሁ ። እኔ ፡ ከወለድሁ ፡ ከሦስት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡
ይህች ፡ ሴት ፡ ደግሞ ፡ ወለደች ፤ እኛ ፡ በቤት ፡
ውስጥ ፡ አብረን ፡ ነበርን ፥ ከሁለታችንም ፡ በቀር ፡
፲፱ ማንም ፡ በቤት ፡ ውስጥ ፡ አልነበረም ። እርስ
ዋም ፡ በላዩ ፡ ስለ ፡ ተኛችበት ፡ የዚህች ፡ ሴት ፡
፳ ልጅ ፡ በሌሊት ፡ ሞተ ። እርስዋም ፡ በእኩለ ፡
ሌሊት ፡ ተነሥታ ፥ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ተኝቼ ፡ ሳለሁ ፥
ልጄን ፡ ከአጠገቤ ፡ ወሰደች ፥ በብብትዋም ፡
አደረገችው ፥ የሞተውንም ፡ ልጅዋን ፡ በእኔ ፡
፳፩ ብብት ፡ አደረገች ። ልጄንም ፡ አጠባ ፡ ዘንድ ፡
በማለዳ ፡ ብነሣ ፥ እነሆ ፥ ሞቶ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡
ግን ፡ ብርሃን ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ተመለከትሁት ፥
፳፪ እነሆም ፥ የወለድሁት ፡ ልጄ ፡ አልነበረም ። ሁለ
ተኛይቱም ፡ ሴት ፡— ደኅነኛው ፡ የእኔ ፡ ልጅ ፡
ነው ፥ የሞተውም ፡ የአንቺ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
አንቺ ፡ እንደምትዪው ፡ አይደለም ፡ አለች ።
ይህችም ፡— የሞተው ፡ የአንቺ ፡ ልጅ ፡ ነው ፥
ደኅነኛውም ፡ የእኔ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ አለች ፤ እን
ዲሁም ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ ይነጋገሩ ፡ ነበር ።
፳፫ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ንጉሡ ፡— ይህች ፡— ደኅ
ነኛው ፡ የእኔ ፡ ልጅ ፡ ነው ፥ የሞተውም ፡ የአ
ንቺ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ትላለች ፤ ያችኛይቱም ፡—
አይደለም ፥ የሞተው ፡ የአንቺ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡
ደኅነኛውም ፡ የእኔ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ትላለች ፡ አለ ።
፳፬ ንጉሡም ፡— ሰይፍ ፡ አምጡልኝ ፡ አለ ፤ ሰይፍም ፡
፳፭ ይዘው ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ፊት ፡ መጡ ። ንጉ
ሡም ፡— ደኅነኛውን ፡ ሕፃን ፡ ለሁለት ፡ ከፍላ
ችሁ ፡ ለአንዲቱ ፡ አንዱን ፡ ክፍል ፥ ለሁለተኛ
፳፮ ይቱም ፡ ሁለተኛውን ፡ ክፍል ፡ስጡ ፡ አለ ። ደኅ
ነኛውም ፡ የነበራት ፡ ሴት ፡ አንጀትዋ ፡ ስለ ፡
ልጅዋ ፡ ናፍቆአልና ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ ደኅነኛ
ውን ፡ ለእርስዋ ፡ ስጣት ፡ እንጂ ፡ አትግደል ፡
ብላ ፡ ለንጉሡ ፡ ተናገረች ። ያችኛይቱ ፡ ግን ፡—
ይከፈል ፡ እንጂ ፡ ለእኔም ፡ ለአንቺም ፡ አይ
፳፯ ሁን ፡ አለች ። ንጉሡም ፡ መልሶ ፡— ይህችኛ
ይቱ ፡ እናቱ ፡ ናትና ፡ ደኅነኛውን ፡ ሕፃን ፡ ለእ
ርስዋ ፡ ስጡአት ፡ እንጂ ፡ አትግደሉት ፡ አለ ።
፳፰ ንጉሡም ፡ የፈረደውን ፡ ፍርድ ፡ እስራኤል ፡
ሁሉ ፡ ሰሙ ፤ ፍርድን ፡ ለማድረግ ፡ የእግዚአ
ብሔር ፡ ጥበብ ፡ እንደ ፡ ነበረበት ፡ አይተዋልና ፡
ንጉሡን ፡ ፈሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ንጉሡም ፡ ሰሎሞን ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡
፪ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ነበር ። የነበሩትም ፡ አለቆች ፡ እነ
ዚህ ፡ ናቸው ፤ የሳዶቅ ፡ ልጅ ፡ ካህኑ ፡ ዓዛርያስ ፥
፫ ጸሐፊዎቹም ፡ የሴባ ፡ ልጆች ፡ ኤልያፍና ፡
አኪያ ፥ ታሪክ ፡ ጸሐፊም ፡ የአሒሉድ ፡ ልጅ ፡
፬ ኢዮሣፍጥ ፥ የዮዳሄም ፡ ልጅ ፡ በናያስ ፡ የሠራ
ዊት ፡ አለቃ ፡ ነበረ ፤ ሳዶቅና ፡ አብያታርም ፡
፭ ካህናት ፡ ነበሩ ፤ የናታንም ፡ ልጅ ፡ ዓዛርያስ ፡
የሹሞች ፡ አለቃ ፡ ነበረ ፤ የናታንም ፡ ልጅ ፡
ዛቡድ ፡ የንጉሡ ፡ አማካሪና ፡ ወዳጅ ፡ ነበረ ፤
፮ አሒሳርም ፡ የቤት ፡ አዛዥ ፥ የዓብዳም ፡ ልጅ ፡
አዶኒራም ፡ አስገባሪ ፡ ነበረ ።

፯ ለንጉሡና ፡ ለቤተ ፡ ሰቡም ፡ ቀለብ ፡ የሚ
ሰጡ ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡
ሹሞች ፡ ለሰሎሞን ፡ ነበሩት ። ከዓመቱ ፡ ውስጥ ፡
አንዱን ፡ ወር ፡ እያንዳንዳቸው ፡ ይቀልቡ ፡ ነበር ።
፰ ስማቸውም ፡ ይህ ፡ ነበረ ፤ በተራራማው ፡ አገር ፡
፱ በኤፍሬም ፡ የሑር ፡ ልጅ ፤ በማቃጽና ፡ በሸ
ዓልቢም ፡ በቤትሳሚስና ፡ በኤሎንቤትሐናን ፡
፲ የዴቀር ፡ ልጅ ፤ በአሩቦት ፡ የሔሴድ ፡ ልጅ ፥
ለእርሱም ፡ ሰኰትና ፡ የአፌር ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡
፲፩ ነበረ ፤ በዶር ፡ አገር ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ የአሚ
ናዳብ ፡ ልጅ ፥ እርሱም ፡ የሰሎሞንን ፡ ልጅ ፡
፲፪ ጣፈትን ፡ አግብቶ ፡ ነበር ፤ ከቤትሳን ፡ ጀምሮ ፡
እስከ ፡ አቤልምሖላና ፡ እስከ ፡ ዮቅምዓም ፡ ማዶ ፡
ድረስ ፡ በታዕናክና ፡ በመጊዶ ፡ በጸርታንም ፡
አጠገብ ፡ በኢይዝራኤል ፡ በታች ፡ ባለው ፡ በቤ
ትሳን ፡ ሁሉ ፡ የአሒሉድ ፡ ልጅ ፡ በዓና ፡ ነበረ ፤
፲፫ በሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡ የጌበር ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፥ ለእ
ርሱም ፡ በገለዓድ ፡ ያሉት ፡ የምናሴ ፡ ልጅ ፡ የኢ
ያዕር ፡ መንደሮች ፡ ነበሩ ፤ ለእርሱም ፡ ደግሞ ፡
በባሳን ፡ በአርጎብ ፡ ዳርቻ ፡ ያሉት ፡ ቅጥርና ፡
የናስ ፡ መወርወሪያዎች ፡ የነበረባቸው ፡ ስድሳ ፡
፲፬ ታላላቅ ፡ ከተሞች ፡ ነበሩበት ፤ በመሃናይም ፡
፲፭ የዒዶ ፡ ልጅ ፡ አሒናዳብ ፤ በንፍታሌም ፡ አኪ
ማአስ ፡ ነበረ ፥ እርሱም ፡ የሰሎሞንን ፡ ልጅ ፡
፲፮ ባስማትን ፡ አግብቶ ፡ ነበር ፤ በአሴርና ፡ በበዓ
፲፯ ሎት ፡ የኩሲ ፡ ልጅ ፡ በዓና ፤ በይሳኮር ፡ የፋሩሖ ፡
፲፰ ልጅ ፡ ኢዮሣፍጥ ፤ በብንያም ፡ የኤላ ፡ ልጅ ፡
፲፱ ሳሚ ፤ በአሞራውያን ፡ ንጉሥ ፡ በሴዎንና ፡ በባ
ሳን ፡ ንጉሥ ፡ በዐግ ፡ አገር ፥ በገለዓድ ፡ አገር ፥
የኡሪ ፡ ልጅ ፡ ጌበር ፡ ነበረ ፤ በዚያችም ፡ ምድር ፡
ላይ ፡ እርሱ ፡ ብቻውን ፡ ሹም ፡ ነበረ ።

፳ ይሁዳና ፡ እስራኤልም ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ አሸዋ ፡
ብዛት ፡ ብዙ ፡ ነበሩ ፤ በልተውም ፡ ጠጥተውም ፡
፳፩ ደስ ፡ ብሎአቸው ፡ ነበር ። ሰሎሞንም ፡ ከወ

ንዙ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ግብጽ ፡ ዳርቻ ፡ እስከ ፡ ፍልስጥኤም ፡ ድረስ ፡ በመንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነግሦ ፡ ነበር ፤ ግብርም ፡ ያመጡለት ፡ ነበር ፥ በዕድሜውም ፡ ሙሉ ፡ ለሰሎሞን ፡ ይገዙ ፡ ነበር ።
፳፪ ለሰሎሞንም ፡ ለቀን ፡ ለቀኑ ፡ ቀለብ ፡ የሚሆን ፡ ሠላሳ ፡ ኮር ፡ መልከም ፡ ዱቄትና ፡
፳፫ ስድሳ ፡ ኮር ፡ መናኛ ፡ ዱቄት ፥ ከዋላና ፡ ከሚዳቋ ፡ ከበረሀ ፡ ፍየልና ፡ ከሰቡ ፡ ወፎች ፡ በቀር ፡ አሥር ፡ ፍሪዳዎች ፡ ሀያም ፡ የተሰማሩ ፡ በሬ
፳፬ ዎች ፡ አንድ ፡ መቶም ፡ በጎች ፡ ነበረ ። ከወንዙ ፡ ወዲህ ፡ ባሉት ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ ከወንዙም ፡ ወዲህ ፡ ባለው ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከቲፍሳ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ጋዛ ፡ ድረስ ፡ ነግሦ ፡ ነበር ፤ በዙሪያውም ፡ ባለው ፡ በሁሉ ፡ ወገን ፡ ሰላም ፡ ሆኖ
፳፭ ለት ፡ ነበር ። በሰሎሞንም ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ይሁዳና ፡ እስራኤል ፡ ከዳን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ቤርሳቤህ ፡ ድረስ ፡ እያንዳንዱ ፡ ከወይኑና ፡ ከበለሱ ፡
፳፮ በታች ፡ ተዘልሎ ፡ ይቀመጥ ፡ ነበር ። ለሰሎሞንም ፡ በአርባ ፡ ሺህ ፡ ጋጥ ፡ የሚገቡ ፡ የሰረገላ ፡ ፈረሶች ፡ አሥራ ፡ ሁለትም ፡ ሺህ ፡ ፈረሰኞች ፡
፳፯ ነበሩት ። እነዚያም ፡ ሹሞች ፡ እያንዳንዱ ፡ በየወሩ ፡ ንጉሡን ፡ ሰሎሞንንና ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ሰሎሞን ፡ ማዕድ ፡ የሚቀርቡትን ፡ ሁሉ ፡ ይቀልቡ ፡ ነበር ፤ ምንም ፡ አያጐድሉም ፡ ነበር ።
፳፰ እያንዳንዱም ፡ እንደ ፡ ደንቡ ፡ ለፈረሶቹና ፡ ለሰጋር ፡ በቅሎች ፡ ገብስና ፡ ጭድ ፡ ወደ ፡ ስፍራቸው ፡ ያመጡ ፡ ነበር ።

፳፱ እግዚአብሔርም ፡ ለሰሎሞን ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ጥበብና ፡ ማስተዋል ፡ በባሕርም ፡ ዳር ፡ እንዳለ ፡
፴ አሸዋ ፡ የልብ ፡ ስፋት ፡ ሰጠው ። የሰሎሞንም ፡ ጥበብ ፡ በምሥራቅ ፡ ካሉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ጥበ
፴፩ ብና ፡ ከግብጽ ፡ ጥበብ ፡ ሁሉ ፡ በለጠ ። ከሰውም ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ከኢይዝራኤላዊው ፡ ከኤታንና ፡ ከማሖል ፡ ልጆች ፡ ከሄማንና ፡ ከከልቀድ ፡ ከደራልም ፡ ይልቅ ፡ ጥበበኛ ፡ ነበረ ። በዙሪያውም ፡
፴፪ ባሉ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ዝናው ፡ ወጣ ። እርሱም ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ምሳሌዎች ፡ ተናገረ ፤ መኃልዩም ፡
፴፫ ሺህ ፡ አምስት ፡ ነበረ ። ስለ ፡ ዛፍም ፡ ከሊባኖስ ፡ ዝግባ ፡ ጀምሮ ፡ በቅጥር ፡ ግንብ ፡ ላይ ፡ እስከሚበቅለው ፡ እስከ ፡ ሂሶጵ ፡ ድረስ ፡ ይናገር ፡ ነበር ፤ ደግሞም ፡ ስለ ፡ አውሬዎችና ፡ ስለ ፡ ወፎች ፡ ስለ ፡ ተንቀሳቃሾችና ፡ ስለ ፡ ዓሣዎች ፡ ይናገር ፡
፴፬ ነበር ። ከአሕዛብም ፡ ሁሉ ፥ ጥበቡንም ፡ ሰምተው ፡ ከነበሩ ፡ ከምድር ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ የሰሎሞንን ፡ ጥበብ ፡ ለመስማት ፡ ሰዎች ፡ ይመጡ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ የጢሮስ ፡ ንጉሥ ፡ ኪራም ፡ ለዳዊት ፡ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ ወዳጁ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፥ ሰሎሞን ፡ በአባቱ ፡ ፋንታ ፡ ንጉሥ ፡ ለመሆን ፡ እንደ ፡ ተቀባ ፡ ሰምቶ ፡ ባሪያዎቹን ፡ ወደ ፡ ሰሎሞን ፡ ሰደደ ።
፪ ሰሎሞንም ፡ ወደ ፡ ኪራም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
፫ ላከ ፡— እግዚአብሔር ፡ ከእግሩ ፡ በታች ፡ እስኪጥልለት ፡ ድረስ ፡ በዙሪያው ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ሰልፍ ፡ አባቴ ፡ ዳዊት ፡ የአምላኩን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ መሥራት ፡ እንዳልቻለ ፡ አንተ ፡ ታውቃለህ ።
፬ አሁንም ፡ አምላኬ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዙሪያዬ ፡ ካሉት ፡ ዕረፍት ፡ ሰጥቶኛል ፤
፭ ጠላትም ፡ ክፉም ፡ ነገር ፡ የለብኝም ። እነሆም ፥ እግዚአብሔር ፡ ለአባቴ ፡ ለዳዊት ፡— በአንተ ፡ ፋንታ ፡ በዙፋንህ ፡ ላይ ፡ የማስቀምጠው ፡ ልጅህ ፡ እርሱ ፡ ለስሜ ፡ ቤት ፡ ይሠራል ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ነገረው ፥ ለአምላኬ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
፮ ስም ፡ ቤት ፡ እሠራ ፡ ዘንድ ፡ አስባለሁ ። አሁንም ፡ ከወገኔ ፡ እንደ ፡ ሲዶናውያን ፡ እንጨት ፡ መቍረጥ ፡ የሚያውቅ ፡ እንደሌለ ፡ ታውቃለህና ፡ የዝግባ ፡ ዛፍ ፡ ከሊባኖስ ፡ ይቈርጡልኝ ፡ ዘንድ ፡ ባሪያዎችህን ፡ እዘዝ ፤ ባሪያዎቼም ፡ ከባሪያዎችህ ፡ ጋር ፡ ይሁኑ ፤ የባሪያዎችህንም ፡ ዋጋ ፡ እንደ ፡ ተናገርኸው ፡ ሁሉ ፡ እሰጥሃለሁ ።
፯ ኪራምም ፡ የሰሎሞንን ፡ ቃል ፡ ሰምቶ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለውና ፡— በዚህ ፡ በታላቅ ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ ጥበበኛ ፡ ልጅ ፡ ለዳዊት ፡ የሰጠ ፡
፰ እግዚአብሔር ፡ ዛሬ ፡ ይመስገን ፡ አለ ። ኪራምም ፡— የላክህብኝን ፡ ሁሉ ፡ ሰማሁ ፤ ስለ ፡ ዝግባውና ፡ ስለ ፡ ጥዱ ፡ እንጨት ፡ ፈቃድህን ፡
፱ ሁሉ ፡ አደርጋለሁ ። ባሪያዎቼ ፡ ከሊባኖስ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ይጐትቱታል ፤ እኔም ፡ በታንኳ ፡ አድርጌ ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡ እያንሳፈፍሁ ፡ አንተ ፡ እስከ ፡ ወሰንኸው ፡ ስፍራ ፡ ድረስ ፡ አደርስልሃለሁ ፥ በዚያም ፡ እፈታዋለሁ ፥ አንተም ፡ ከዚያ ፡ ታስወስደዋለህ ፤ አንተም ፡ ፈቃዴን ፡ ታደርጋለህ ፥ ለቤቴም ፡ ቀለብ ፡ የሚሆነውን ፡ ትሰጠኛለህ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ሰሎሞን ፡ ላከ ።
፲ እንዲሁም ፡ ኪራም ፡ የዝግባውንና ፡ የጥዱን ፡ እንጨት ፡ እንደሚሻው ፡ ያህል ፡ ሁሉ ፡ ለሰሎሞን ፡ ይሰ
፲፩ ጠው ፡ ነበር ። ሰሎሞንም ፡ ለኪራም ፡ ስለ ፡ ቤቱ ፡ ቀለብ ፡ ሀያ ፡ ሺህ ፡ የቆሮስ ፡ መስፈሪያ ፡ ስንዴ ፡ ሀያ ፡ ኮርም ፡ ጥሩ ፡ ዘይት ፡ ይሰጠው ፡ ነበር ፤ ሰሎሞንም ፡ ለኪራም ፡ በየዓመቱ ፡
፲፪ ይህን ፡ ይሰጥ ፡ ነበር ። እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ነገረው ፡ ለሰሎሞን ፡ ጥበብን ፡ ሰጠው ፤ በኪራምና ፡ በሰሎሞንም ፡ መካከል ፡ ሰላም ፡ ነበረ ፤ ሁለቱም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ተጋቡ ።
፲፫ ሰሎሞንም ፡ ከእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ገባሮቹን ፡ መርጦ ፡ አወጣ ፤ የገባሮቹም ፡ ቍጥር ፡ ሠላሳ ፡
፲፬ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ነበረ ። በየወሩም ፡ እያከታተለ ፡ ወደ ፡ ሊባኖስ ፡ አሥር ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ይሰድድ ፡ ነበር ፤ አንድ ፡ ወርም ፡ በሊባኖስ ፡ ሁለት ፡ ወርም ፡ በቤታቸው ፡ ይቀመጡ ፡ ነበር ። አዶ
፲፭ ኒራምም ፡ አስገባሪ ፡ ነበረ ። ሰሎሞንም ፡ ሰባ ፡ ሺህ ፡ ተሸካሚዎች ፥ ሰማንያ ፡ ሺህም ፡ በተራራው ፡ ላይ ፡ የሚጠርቡ ፡ ጠራቢዎች ፡ ነበሩት ።
፲፮ ይኸውም ፡ በሠራተኛው ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ ከተሾሙት ፡ ከሦስት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡
፲፯ ሌላ ፡ ነው ። ንጉሡም ፡ ታላላቅ ፡ ምርጥ ፡ ምርጥ ፡ ድንጋዮችን ፡ ይቈፍሩና ፡ ይጠርቡ ፡

ዘንድ ፡ ለቤቱም ፡ መሠረት ፡ ይረበርቡት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ። ፲፰ የሰሎሞንና ፡ የኪራምም ፡ አናጢዎች ፡ ጌባላውያንም ፡ ወቀሩአቸው ÷ ቤቱንም ፡ ለመሥራት ፡ እንጨቱንና ፡ ድንጋዮቹን ፡ አዘጋጁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ከወጡ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ ዓመት ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ÷ ሰሎሞን ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ በነገሠ ፡ በአራተኛው ፡ ዓመት ÷ ዚፍ ፡ በሚባለው ፡ በሁለተኛው ፡ ወር ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ መሥራት ፡ ጀመረ ። ፪ ንጉሡ ፡ ሰሎሞንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሠራው ፡ ቤት ፡ ርዝመቱ ፡ ስድሳ ፡ ክንድ ÷ ወርዱም ፡ ሀያ ፡ ክንድ ÷ ቁመቱም ፡ ሠላሳ ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፫ በመቅደሱም ፡ ፊት ፡ ወለል ፡ ነበረ ፤ ርዝመቱም ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ወርድ ፡ ሀያ ፡ ክንድ ÷ ወርዱም ፡ ከቤቱ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ አሥር ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፬ ለቤቱም ፡ በዓይነ ፡ ርግብ ፡ የተዘጉ ፡ መስኮቶች ፡ አደረገ ። ፭ በቤቱም ፡ ግንብ ፡ ዙሪያ ÷ በመቅደሱና ፡ በቅድስተ ፡ ቅዱሳኑ ፡ ግንብ ፡ ዙሪያ ÷ ደርብ ፡ ሠራ ÷ ፮ በዙሪያውም ፡ ጓዳዎች ፡ አደረገ ። የታችኛውም ፡ ደርብ ፡ ወርዱ ፡ አምስት ፡ ክንድ ÷ የመካከለኛው ፡ ደርብ ፡ ወርዱ ፡ ስድስት ፡ ክንድ ÷ የሦስተኛውም ፡ ደርብ ፡ ወርዱ ፡ ሰባት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ሰረገሎቹ ፡ በቤቱ ፡ ግንብ ፡ ውስጥ ፡ እንዳይገቡ ፡ ከቤቱ ፡ ግንብ ፡ ውጭ ፡ ዓረፍቶች ፡ አደረገ ። ፯ ቤቱም ፡ በተሠራ ፡ ጊዜ ፡ ፈጽመው ፡ በተወቀሩ ፡ ድንጋዮች ፡ ተሠራ ፤ በተሠራም ፡ ጊዜ ፡ መራጃና ፡ መጥረቢያ ፡ የብረትም ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ አልተሰማም ። ፰ የታችኛውም ፡ ደርብ ፡ ጓዳዎች ፡ በር ፡ በቤቱ ፡ ቀኝ ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ። ከዚያም ፡ ወደ ፡ መካከለኛው ፡ ደርብ ÷ ከመካከለኛውም ፡ ወደ ፡ ሦስተኛው ፡ ደርብ ፡ በመውጫ ፡ ያስወጣ ፡ ነበር ። ፱ ቤቱንም ፡ ሠርቶ ፡ ፈጸመው ፤ በዝግባው ፡ ሰረገሎችና ፡ ሳንቃዎች ፡ ከደነው ። ፲ በቤቱም ፡ ሁሉ ፡ ዙሪያ ፡ ቁመታቸው ፡ አምስት ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፡ ደርቦች ፡ ሠራ ፤ ከቤቱም ፡ ጋር ፡ በዝግባ ፡ እንጨት ፡ አጋጠማቸው ።

፲፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ሰሎሞን ፡ ፲፪ መጣ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡— ስለዚህ ፡ ስለምትሠራው ፡ ቤት ፡ በሥርዓቴ ፡ ብትሄድ ÷ ፍርዴንም ፡ ብታደርግ ÷ ትመላለስበትም ፡ ዘንድ ፡ ትእዛዜን ፡ ሁሉ ፡ ብትጠብቅ ÷ ለአባትህ ፡ ለዳዊት ፡ የነገርሁትን ፡ ቃል ፡ ፲፫ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አጸናለሁ ። በእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ እኖራለሁ ÷ ሕዝቤንም ፡ እስራኤልን ፡ አልጥልም ።

፲፬ ሰሎሞንም ፡ ቤቱን ፡ ሠራው ÷ ፈጸመውም ። ፲፭ የቤቱንም ፡ ግንብ ፡ ውስጡን ፡ በዝግባ ፡ ሳንቃ ፡ ለበጠ ፤ ከቤቱም ፡ መሠረት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ጣራው ፡ ድረስ ፡ ውስጡን ፡ በእንጨት ፡ ለበጠው ፤ ደግሞም ፡ የቤቱን ፡ ወለል ፡ በጥድ ፡ እንጨት ፡ ከደነው ። ፲፮ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ኋለኛውን ፡ ሀያውን ፡ ክንድ ፡ በዝግባ ፡ እንጨት ፡ ጋረደው ። ፲፯ በቅድስተ ፡ ቅዱሳኑ ፡ ፊት ፡ ያለውም ፡ መቅደስ ፡ ርዝመቱ ፡ አርባ ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፲፰ የቤቱንም ፡ ውስጥ ፡ በተጐበጐበና ፡ በፈነዳ ፡ አበባ ፡ በተቀረጸ ፡ ዝግባ ፡ ለበጠው ፤ ሁሉም ፡ ዝግባ ፡ ነበረ ፤ ድንጋዩም ፡ አልታየም ፡ ነበር ። ፲፱ በዚያም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ ያኖር ፡ ዘንድ ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ቅድስተ ፡ ቅዱሳኑን ፡ አበጀ ። ፳ የቅድስተ ፡ ቅዱሳንም ፡ ርዝመት ፡ ሀያ ፡ ክንድ ÷ ስፋቱም ፡ ሀያ ፡ ክንድ ÷ ቁመቱም ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፤ በጥሩ ፡ ወርቅም ፡ ለበጠው ። ፳፩ በቅድስተ ፡ ቅዱሳኑም ፡ ፊት ፡ ከዝግባ ፡ የተሠራ ፡ መሠዊያ ፡ አደረገ ፤ በጥሩ ፡ ወርቅም ፡ ለበጠው ። ፳፪ ቤቱንም ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሞ ፡ በወርቅ ፡ ለበጠው ፤ በቅድስተ ፡ ቅዱሳኑም ፡ ፊት ፡ የነበረውን ፡ መሠዊያ ፡ ሁሉ ፡ በወርቅ ፡ ለበጠው ።

፳፫ በቅድስተ ፡ ቅዱሳኑም ፡ ውስጥ ፡ ቁመታቸው ፡ አሥር ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፡ ከወይራ ፡ እንጨት ፡ ሁለት ፡ ኪሩቤል ፡ ሠራ ። ፳፬ የኪሩብም ፡ አንደኛው ፡ ክንፍ ፡ አምስት ፡ ክንድ ÷ የኪሩብም ፡ ሁለተኛው ፡ ክንፍ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፤ ከአንደኛው ፡ ክንፍ ፡ ጫፍ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሁለተኛው ፡ ክንፍ ፡ ጫፍ ፡ ድረስ ፡ አሥር ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፳፭ ሁለተኛውም ፡ ኪሩብ ፡ አሥር ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፤ ሁለቱም ፡ ኪሩቤል ፡ አንድ ፡ ልክና ፡ አንድ ፡ መልክ ፡ ነበረ ። ፳፮ የአንዱ ፡ ኪሩብ ፡ ቁመት ፡ አሥር ፡ ክንድ ፡ ነበረ ÷ የሁለተኛውም ፡ ኪሩብ ፡ እንዲሁ ፡ ነበረ ። ፳፯ ኪሩቤልንም ፡ በውስጠኛው ፡ ቤት ፡ አኖራቸው ፤ የኪሩቤልም ፡ ክንፎቻቸው ፡ ተዘርግተው ፡ ነበር ፤ የአንዱም ፡ ኪሩብ ፡ ክንፍ ፡ አንደኛውን ፡ ግንብ ፡ ይነካ ፡ ነበር ÷ የሁለተኛውም ፡ ኪሩብ ፡ ክንፍ ፡ ሁለተኛውን ፡ ግንብ ፡ ይነካ ፡ ነበር ፤ የሁለቱም ፡ ክንፎች ፡ በቤቱ ፡ መካከል ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ይነካኩ ፡ ነበር ። ፳፰ ኪሩቤልንም ፡ በወርቅ ፡ ለበጣቸው ።

፳፱ በቤቱም ፡ ግንብ ፡ ሁሉ ፡ ዙሪያ ፡ በውስጥና ፡ በውጭ ፡ የኪሩቤልና ፡ የዘንባባ ፡ ዛፍ ፡ የፈነዳም ፡ አበባ ፡ ምስል ፡ ቀረጸ ። ፴ የቤቱንም ፡ ወለል ፡ በውስጥና ፡ በውጭ ፡ በወርቅ ፡ ለበጠ ። ፴፩ ለቅድስተ ፡ ቅዱሳኑም ፡ መግቢያ ፡ ከወይራ ፡ እንጨት ፡ ደጆች ፡ ሠራ ፤ መድረኩንና ፡ መቃኖቹን ፡ ደፉንም ፡ አምስት ፡ ማዕዘን ፡ አደረገ ። ፴፪ ሁለቱንም ፡ ደጆች ፡ ከወይራ ፡ እንጨት ፡ ሠራ ፤ የኪሩቤልንና ፡ የዘንባበ ፡ ዛፍ ፡ የፈነዳም ፡ አበባ ፡ ምስል ፡ ቀረጸባቸው ÷ በወርቅም ፡ ለበጣቸው ፤ ኪሩቤልንና ፡ የዘንባባውን ፡ ዛፍ ፡ በወርቅ ፡ ለበጣቸው ። ፴፫ እንዲሁም ፡ ለመቅደሱ ፡ መግቢያ ፡ ከወይራ ፡ እንጨት ፡ አራት ፡ ማዕዘን ፡ መቃን ፡ አደረገ ። ፴፬ ሁለቱንም ፡ ደጆች ፡ ከጥድ ፡ እንጨት ፡ ሠራ ፤ አንዱ ፡ ደጅ ፡ በማጠፊያ ፡ ከተያያዙ ፡ ከሁ

ለት ፡ ሰንቃ ፡ ተደረገ ፥ ሁለተኛውም ፡ ደጅ ፡ በማጠፊያ ፡ ከተያያዘ ፡ ከሁለት ፡ ሰንቃ ፡ ተደረገ ። ፴፭ የኪሩቤልንና ፡ የዘንባባ ፡ ዛፍ ፡ የፈነዳም ፡ አበባ ፡ ምስል ፡ ቀረጸባቸው ፤ በተቀረጸውም ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ በወርቅ ፡ ለበጣቸው ። ፴፮ የውስጠኛውንም ፡ አደባባይ ፡ ቅጥር ፡ ሦስቱን ፡ ተራ ፡ በተጠረበ ፡ ድንጋይ ፥ አንዱንም ፡ ተራ ፡ በዝግባ ፡ ሰንቃ ፡ ሠራው ።

፴፯ በአራተኛው ፡ ዓመት ፡ ዚፍ ፡ በሚባል ፡ ወር ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ተመሠረተ ። ፴፰ በአሥራ ፡ አንደኛውም ፡ ዓመት ፡ ቡል ፡ በሚባል ፡ በስምንተኛው ፡ ወር ፡ ቤቱ ፡ እንደ ፡ ክፍሎቹና ፡ እንደ ፡ ሥርዓቱ ፡ ሁሉ ፡ ተጨረሰ ። በሰባትም ፡ ዓመት ፡ ውስጥ ፡ ሠራው ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ሰሎሞንም ፡ የራሱን ፡ ቤት ፡ በአሥራ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ሠራ ፥ የቤቱንም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ጨረሰ ። ፪ የሊባኖስ ፡ ዱር ፡ ቤት ፡ የሚባል ፡ ቤትን ፡ ሠራ ፤ ርዝመቱንም ፡ መቶ ፡ ክንድ ፥ ስፋቱንም ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፥ ቁመቱንም ፡ ሠላሳ ፡ ክንድ ፡ አደረገ ፤ የዝግባም ፡ እንጨት ፡ በሦስት ፡ ተራ ፡ በተሠሩ ፡ አዕማድ ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፤ በአዕማዱም ፡ ላይ ፡ የዝግባ ፡ እንጨት ፡ አግዳሚ ፡ ሰረገሎች ፡ ነበሩ ። ፫ በአዕማዱም ፡ ላይ ፡ በነበሩ ፡ አግዳሚዎች ፡ ቤቱ ፡ በዝግባ ፡ ሰንቃ ፡ ተሸፍኖ ፡ ነበር ፤ አዕማዱም ፡ በአንዱ ፡ ተራ ፡ አሥራ ፡ አምስት ፥ በአንዱ ፡ ተራ ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡ እየሆኑ ፡ አርባ ፡ አምስት ፡ ነበሩ ። ፬ መስኮቶቹም ፡ በሦስት ፡ ተራ ፡ ነበሩ ፥ መስኮቶቹም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ይተያዩ ፡ ነበር ። ፭ ደጆቹና ፡ መስኮቶቹም ፡ ሁሉ ፡ አራት ፡ ማዕዘን ፡ ነበሩ ፤ መስኮቶቹም ፡ በሦስት ፡ ተራ ፡ ሆነው ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ይተያዩ ፡ ነበር ። ፮ አዕማዱም ፡ ያሉበቱን ፡ ቤት ፡ ሠራ ፤ ርዝመቱም ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፥ ስፋቱም ፡ ሠላሳ ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፤ በእርሱም ፡ ፊት ፡ ደግሞ ፡ አዕማድና ፡ መድረክ ፡ ያሉበት ፡ ወለል ፡ ነበረ ። ፯ ደግሞም ፡ የሚፈርድበት ፡ ዙፋኑን ፡ ያለበትን ፡ የፍርድ ፡ ቤት ፡ አደረገ ። ከወለሉም ፡ አንሥቶ ፡ እስከ ፡ ጣራው ፡ ድረስ ፡ በዝግባ ፡ እንጨት ፡ ተሸፍኖ ፡ ነበር ። ፰ ከፍርድ ፡ ሰቀላ ፡ ወደ ፡ ውስጥ ፥ በሌላውም ፡ አደባባይ ፡ ውስጥ ፡ የነበረውን ፡ መኖሪያ ፡ ቤት ፡ እንዲሁ ፡ ሠራ ። እንደዚሁም ፡ ያለ ፡ ቤት ፡ ሰሎሞን ፡ ላገባት ፡ ለፈርዖን ፡ ልጅ ፡ ቤት ፡ ሠራ ።

፱ እነዚህም ፡ ሁሉ ፡ ከመሠረቱ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ጉልላቱ ፡ ድረስ ፡ በጥሩ ፡ በተጠረበና ፡ በውስጥና ፡ በውጭ ፡ በልክ ፡ በተከረከመ ፡ ድንጋይ ፡ ተሠርተው ፡ ነበር ፤ በውጭውም ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ አደባባይ ፡ ድረስ ፡ እንዲሁ ፡ ነበረ ። ፲ መሠረቱም ፡ አሥር ፡ ወይም ፡ ስምንት ፡ ክንድ ፡ በሆነ ፡ በጥሩና ፡ በታላቅ ፡ ድንጋይ ፡ ተሠርቶ ፡ ነበር ። ፲፩ በላዩም ፡ ልክ ፡ ሆኖ ፡ የተከረከመ ፡ ጥሩ ፡ ድንጋይና ፡ የዝግባ ፡ ሰንቃ ፡ ነበረ ። ፲፪ በታላቁም ፡ አደባባይ ፡ ዙሪያ ፡ የነበረው ፡ ቅጥር ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ውስጠኛው ፡ አደባባይ ፡ ቅጥርና ፡ እንደ ፡ ቤቱ ፡ ወለል ፡ ሦስቱ ፡ ተራ ፡ በተጠረበ ፡ ድንጋይ ፡ አንዱም ፡ ተራ ፡ በዝግባ ፡ ሰንቃ ፡ ተሠርቶ ፡ ነበር ።

፲፫ ንጉሡም ፡ ሰሎሞን ፡ ልኮ ፡ ኪራምን ፡ ከጢሮስ ፡ አስመጣ ። ፲፬ እርሱም ፡ ከንፍታሌም ፡ ወገን ፡ የነበረች ፡ የባል ፡ አልባ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፥ አባቱም ፡ የጢሮስ ፡ ሰው ፡ ናስ ፡ ሠራተኛ ፡ ነበረ ፤ የናስንም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ በጥበብና ፡ በማስተዋል ፡ በብልሃትም ፡ ተሞልቶ ፡ ነበር ። ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ወደ ፡ ሰሎሞን ፡ መጥቶ ፡ ሥራውን ፡ ሁሉ ፡ ሠራ ። ፲፭ ሁለቱን ፡ የናስ ፡ አዕማድ ፡ አደረገ ፤ የአንዱም ፡ ዓምድ ፡ ቁመት ፡ አሥራ ፡ ስምንት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ የዙሪያውም ፡ መጠን ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፤ የዓምዱም ፡ ውፍረት ፡ አንድ ፡ ጋት ፡ ነበረ ፥ ውስጡ ፡ ክፍትም ፡ ነበረ ። ሁለተኛውም ፡ ዓምድ ፡ እንዲሁ ፡ ነበረ ። ፲፮ በሁለቱም ፡ አዕማድ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ እንዲቀመጡ ፡ ከፈሰሰ ፡ ናስ ፡ ሁለት ፡ ጉልላት ፡ ሠራ ፤ የአንዱም ፡ ጉልላት ፡ ቁመት ፡ አምስት ፡ ክንድ ፥ የሁለተኛውም ፡ ጉልላት ፡ ቁመት ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፲፯ በአዕማዱም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ የነበሩትን ፡ ጉልላቶች ፡ ይሸፍኑ ፡ ዘንድ ፡ ሁለት ፡ እንደ ፡ መርበብ ፡ ሥራ ፡ አደረገ ፤ አንዱም ፡ መርበብ ፡ ለአንዱ ፡ ጉልላት ፡ ሁለተኛውም ፡ መርበብ ፡ ለሁለተኛው ፡ ጉልላት ፡ ነበረ ። ፲፰ ሮማኖችንም ፡ ሠራ ፤ በአንድ ፡ ጉልላት ፡ ዙሪያ ፡ በተራ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሮማኖች ፡ ነበሩ ፥ በአንድም ፡ መርበብ ፡ ላይ ፡ ሁለት ፡ ተራ ፡ ነበረ ፤ እንዲሁም ፡ ለሁለተኛው ፡ ጉልላት ፡ አደረገ ። ፲፱ በወለሉም ፡ አዕማድ ፡ በነበሩት ፡ ጉልላቶች ፡ ላይ ፡ የሱፍ ፡ አበባ ፡ የሚመስል ፡ ሥራ ፡ አራት ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ቀረጸ ። ፳ በሁለቱም ፡ አዕማድ ፡ በነበሩት ፡ ጉልላቶች ፡ ላይ ፡ በመርበቡ ፡ ሥራ ፡ አጠገብ ፡ ሮማኖቹን ፡ አደረገ ። ፳፩ አዕማዱንም ፡ በመቅደሱ ፡ ወለል ፡ አጠገብ ፡ አቆማቸው ፤ የቀኙንም ፡ ዓምድ ፡ አቁሞ ፡ ያቁም ፡ ብሎ ፡ ጠራው ፤ የግራውንም ፡ ዓምድ ፡ አቁሞ ፡ በለዝ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ። ፳፪ በአዕማዱም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ የሱፍ ፡ አበባ ፡ የሚመስል ፡ ሥራ ፡ ነበረ ፤ እንዲሁም ፡ የአዕማዱ ፡ ሥራ ፡ ተጨረሰ ።

፳፫ ከፈሰሰም ፡ ናስ ፡ ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ አሥር ፡ ክንድ ፥ ቁመቱም ፡ አምስት ፡ ክንድ ፥ በዙሪያውም ፡ ሠላሳ ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፡ ክብ ፡ ኩሬ ፡ ሠራ ። ፳፬ ከከንፈሩም ፡ በታች ፡ ለአንድ ፡ ክንድ ፡ አሥር ፡ ለአንድ ፡ ክንድም ፡ አሥር ፡ ጉብጉቦች ፡ አዟረበት ፤ እርሱም ፡ በቀለጠ ፡ ጊዜ ፡ ጉብጉቦቹ ፡ በሁለት ፡ ተራ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አብረው ፡ ቀልጠው ፡ ነበር ። ፳፭ ኩሬውም ፡ በአሥራ ፡ ሁለት ፡ በሬዎች ፡ ምስል ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ፤ ከእነርሱም ፡ ሦስቱ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፥ ሦስቱም ፡ ወደ ፡

ምዕራብ ፥ ሦስቱም ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፥ ሦስቱም ፡
ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ። ኵሬውም ፡
በላያቸው ፡ ነበረ ፥ የሁሉም ፡ ጀርባቸው ፡ በስተ ፡
፳፮ ውስጥ ፡ ነበረ ። ውፍረቱም ፡ አንድ ፡ ጋት ፡
ነበረ ፤ ከንፈሩም ፡ እንደ ፡ ጽዋ ፡ ከንፈር ፡ ተሠ
ርቶ ፡ ነበር ፤ እንደ ፡ ሱፍ ፡ አበባዎች ፡ ሆኖ ፡
ተከርክሞ ፡ ነበር ። ሁለት ፡ ሺህም ፡ የባዶስ ፡
መስፈሪያ ፡ ይይዝ ፡ ነበር ።

፳፯ አሥርም ፡ የናስ ፡ መቀመጫዎች ፡ ሠራ ፤ የአን
ዱም ፡ መቀመጫ ፡ ርዝመት ፡ አራት ፡ ክንድ ፥
ወርዱም ፡ አራት ፡ ክንድ ፥ ቁመቱም ፡ ሦስት ፡
፳፰ ክንድ ፡ ነበረ ። የመቀመጫውም ፡ ሥራ ፡ እን
ዲህ ፡ ነበረ ፤ በክፈፎችም ፡ መካከል ፡ ያለው ፡
፳፱ ሰንበር ፡ ይመስል ፡ ነበር ። በክፈፎቹም ፡ መካ
ከል ፡ በነበሩ ፡ ሰንበሮች ፡ ላይ ፡ አንበሳዎችና ፡
በሬዎች ፡ ኪሩቤልም ፡ ነበሩ ፤ እንዲሁም ፡ በክ
ፈፎቹ ፡ ላይ ፡ ነበረ ፤ ከአንበሳዎቹና ፡ ከበሬዎቹ ፡
በታች ፡ ሻኵራ ፡ የሚመስል ፡ ተንጠልጥሎ ፡
፴ ነበር ። በየመቀመጫዎቹም ፡ ሁሉ ፡ አራት ፡
የናስ ፡ መንኰራኵሮች ፡ ነበሩባቸው ፤ መንኰ
ራኵሮቹም ፡ የሚዞሩበትን ፡ የናስ ፡ ወስከምት ፡
ሠራ ፤ ከመታጠቢያውም ፡ ሰን ፡ በታች ፡ በአ
ራቱ ፡ ማዕዘን ፡ በኩል ፡ አራት ፡ በምስል ፡ የፈ
፴፩ ሰሱ ፡ እግሮች ፡ ነበሩ ። በክፈፉም ፡ ውስጥ ፡ የነ
በረ ፡ አንገት ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፤ አንገቱም ፡
ድቡልቡል ፡ ነበረ ፥ ቁመቱም ፡ ክንድ ፡ ተኩል ፡
ነበረ ። በአንገቱም ፡ ላይ ፡ ቅርጽ ፡ ነበረበት ፤
ክፈፉ ፡ ግን ፡ አራት ፡ ማዕዘን ፡ ነበረ ፡ እንጂ ፡
፴፪ ድቡልቡል ፡ አልነበረም ። አራቱም ፡ መንኰራ
ኵሮች ፡ ከሰንበሮቹ ፡ በታች ፡ ነበሩ ፤ የመንኰራ
ኵሮቹም ፡ ወስከምት ፡ በመቀመጫው ፡ ውስጥ ፡
ነበረ ፤ የመንኰራኵሩም ፡ ቁመት ፡ ክንድ ፡ ተኩል ፡
፴፫ ነበረ ። የመንኰራኵሮቹም ፡ ሥራ ፡ እንደ ፡
ሰረገላ ፡ መንኰራኵር ፡ ነበረ ፥ ወስከምቶቹና ፡
የመንኰራኵሮቹ ፡ ክፈፍ ፡ ቅትርቶቹም ፡ ወስ
ከምቱም ፡ የሚገባበት ፡ ቧምቧ ፡ ሁሉ ፡ በም
፴፬ ስል ፡ የፈሰሰ ፡ ነበር ። በእያንዳንዱም ፡ መቀ
መጫ ፡ በአራቱ ፡ ማዕዘን ፡ በኩል ፡ አራት ፡ ደገ
ፉዎች ፡ ነበሩ ፤ ደገፉዎቹም ፡ ከመቀመጫው ፡
፴፭ ጋር ፡ ተገጥመው ፡ ነበር ። በመቀመጫውም ፡
ላይ ፡ ስንዝር ፡ የሚሆን ፡ ድቡልቡል ፡ ነገር ፡
ነበረ ፤ በመቀመጫውም ፡ ላይ ፡ የነበሩ ፡ መያ
ዦዎችና ፡ ሰንበሮች ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይጋጠሙ ፡
፴፮ ነበር ። በመያዣውና ፡ በሰንበሮቹ ፡ ላይ ፡ ኪሩ
ቤልንና ፡ አንበሳዎችን ፡ የዘንባባውንም ፡ ዛፍ ፡
እንደ ፡ መጠናቸው ፡ ቀረጸ ፥ በዙሪያውም ፡
፴፯ ሻኵራ ፡ አደረገ ። እንዲሁ ፡ አሥሩን ፡ መቀመ
ጫዎች ፡ ሠራ ፤ ሁሉም ፡ በምስልና ፡ በመጠን ፡
በንድፍም ፡ ትክክሎች ፡ ነበሩ ።

፴፰ አሥሩንም ፡ የናስ ፡ መታጠቢያ ፡ ሰን ፡ ሠራ ፤
አንዱ ፡ መታጠቢያ ፡ ሰን ፡ አርባ ፡ የባዶስ ፡
መስፈሪያ ፡ ያነሣ ፡ ነበር ፤ እያንዳንዱም ፡ መታ
ጠቢያ ፡ ሰን ፡ አራት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፤ በአሥ
ሩም ፡ መቀመጫዎች ፡ ላይ ፡ በእያንዳንዱ ፡
አንድ ፡ አንድ ፡ መታጠቢያ ፡ ሰን ፡ ይቀመጥ ፡
፴፱ ነበር ። አምስቱንም ፡ መቀመጫዎች ፡ በቤቱ ፡
ቀኝ ፥ አምስቱንም ፡ በቤቱ ፡ ግራ ፡ አኖራቸው ፤
ኵሬውንም ፡ በቤቱ ፡ ቀኝ ፡ በአዜብ ፡ በኩል ፡
አኖረው ።

፵ ኪራምም ፡ ምንቸቶችንና ፡ መጫሪያዎችን ፡
ድስቶችንም ፡ ሠራ ፤ ኪራምም ፡ ለንጉሡ ፡ ለሰ
ሎሞን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የሠራውን ፡
፵፩ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ጨረሰ ። ሁለቱም ፡ አዕማድ ፥
በአዕማዱም ፡ ላይ ፡ የነበሩትን ፡ ኩብ ፡ የሚመስ
ሉትን ፡ ጕልላቶች ፥ በአዕማዱም ፡ ላይ ፡ የነበ
ሩትን ፡ ሁለቱን ፡ ጕልላቶች ፡ የሚሸፍኑትን ፡
፵፪ ሁለቱን ፡ መርበቦች ፥ በአዕማዱም ፡ ላይ ፡ የነበ
ሩትን ፡ ሁለቱን ፡ ጕልላቶች ፡ ይሸፍኑ ፡ ዘንድ ፡
ለእያንዳንዱ ፡ መርበብ ፡ በሁለት ፡ በሁለት ፡ ተራ ፡
አድርጎ ፡ ለሁለቱ ፡ መርበቦች ፡ አራት ፡ መቶ ፡
፵፫ ሮማኖች ፡ አደረገ ። አሥሩንም ፡ መቀመጫ
ዎች ፥ በመቀመጫዎችም ፡ ላይ ፡ የሚቀመጡ
፵፬ ትን ፡ አሥሩን ፡ መታጠቢያ ፡ ሰን ፥ አንዱንም ፡
ኵሬ ፥ ከኵሬውም ፡ በታች ፡ የሚሆኑትን ፡
፵፭ አሥራ ፡ ሁለቱን ፡ በሬዎች ፥ ምንቸቶቹንም ፥
መጫሪያዎቹንም ፥ ድስቶቹንም ፡ አደረገ ።
ኪራምም ፡ ለንጉሡ ፡ ለሰሎሞን ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ቤት ፡ የሠራው ፡ ይህ ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡
፵፮ የጋለ ፡ ናስ ፡ ነበረ ። በዮርዳኖስ ፡ ሜዳ ፡ በሱክ
ትና ፡ በጻርታን ፡ መካከል ፡ ባለው ፡ በወፍራሙ ፡
፵፯ መሬት ፡ ውስጥ ፡ አስፈሰሰው ። ሰሎሞንም ፡
ዕቃውን ፡ ሁሉ ፡ ሳያስመዝን ፡ አኖረ ፤ የናሱም ፡
ሚዛን ፡ ከብዛቱ ፡ የተነሣ ፡ አይቈጠርም ፡ ነበር ።

፵፰ ሰሎሞንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የነበረ
ውን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ አሠራ ፤ የወርቁን ፡ መሠ
ዊያ ፥ የገጹም ፡ ኅብስት ፡ የነበረበትን ፡ የወርቅ ፡
፵፱ ገበታ ፥ በቅድስተ ፡ ቅዱሳኑ ፡ ፊት ፡ አምስቱ ፡
በቀኝ ፡ አምስቱም ፡ በግራ ፡ የሚቀመጡትን ፡
ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ የተሠሩትንም ፡ መቅረዞች ፥
የወርቁንም ፡ አበባዎችና ፡ ቀንዲሎች ፡ መኰስ
፶ ተሪያዎችም ፥ ከጥሩ ፡ ወርቅም ፡ የተሠሩትን ፡
ጽዋዎችና ፡ ጕጠቶች ፥ ድስቶቹንና ፡ ጭልፋዎ
ቹንም ፥ ማንደጃዎቹንም ፥ ለውስጠኛውም ፡
ቤት ፡ ለቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፡ ደጆች ፡ ለቤተ ፡
መቅደሱም ፡ ደጆች ፡ የሚሆኑትን ፡ የወርቅ ፡
ማጠፊያዎች ፡ አሠራ ።

፶፩ እንዲሁ ፡ ንጉሡ ፡ ሰሎሞን ፡ በእግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ ውስጥ ፡ ያሠራው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ተፈ
ጸመ ። አባቱም ፡ ዳዊት ፡ የቀደሰውን ፥ ብርና ፡
ወርቅ ፡ ዕቃም ፥ ሰሎሞን ፡ አገባ ፥ በእግዚአ
ብሔርም ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ በነበሩ ፡ ግምጃ ፡
ቤቶች ፡ አኖረው ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ ሰሎሞንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
ታቦት ፡ ከዳዊት ፡ ከተማ ፡ ከጽዮን ፡ ያወጡ ፡
ዘንድ ፡ የእስራኤልን ፡ ሽማግሌዎችና ፡ የነገድ ፡
አለቆችን ፡ ሁሉ ፥ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ የአ

ባቶቻቸውን ፡ ቤቶች ፡ መሳፍንት ፣ ንጉሡ ፡ ሰሎሞን ፡ ወዳለበት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሰበሰባቸው ። ፪ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ኤታኒም ፡ በሚባል ፡ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ በበዓሉ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ሰሎሞን ፡ ተከማቹ ። ፫ የእስራኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሁሉ ፡ መጡ ፤ ፬ ካህናቱም ፡ ታቦቱን ፡ አነሡ ። የእግዚአብሔርንም ፡ ታቦት ፣ የመገናኛውንም ፡ ድንኳን ፣ በድንኳኑም ፡ ውስጥ ፡ የነበረውን ፡ የተቀደሰውን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ አመጡ ፤ እነዚህንም ፡ ሁሉ ፡ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑ ፡ አመጡ ። ፭ ንጉሡም ፡ ሰሎሞን ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የተሰበሰቡ ፡ የእስራኤል ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በታቦቱ ፡ ፊት ፡ ሆነው ፣ ከብዛታቸው ፡ የተነሣ ፡ የማይቈጠሩትንና ፡ የማይመጠኑትን ፡ በጎችና ፡ በሬዎች ፡ ይሠዉ ፡ ነበር ። ፮ ካህናቱም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ በቤቱ ፡ በቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፡ ውስጥ ፡ ከኪሩቤል ፡ ክንፍ ፡ በታች ፡ ወደ ፡ ነበረው ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ አመጡት ። ፯ ኪሩቤልም ፡ በታቦቱ ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ ክንፎቻቸውን ፡ዘርግተው ፡ ነበር ፤ ኪሩቤልም ፡ ታቦቱንና ፡ መሎጊያዎቹን ፡ በስተ ፡ ላይ ፡ በኩል ፡ ሸፍነው ፡ ነበር ። ፰ መሎጊያዎቹም ፡ ረጃጅሞች ፡ ነበሩ ፤ በቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፡ ፊት ፡ ከመቅደሱ ፡ ውስጥ ፡ ጫፎቻቸው ፡ ይታዩ ፡ ነበር ፤ በውጭ ፡ ያለ ፡ ግን ፡ አያያቸውም ፡ ነበር ፤ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ አሉ ። ፱ በታቦቱም ፡ ውስጥ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፣ እግዚአብሔርም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ባደረገ ፡ ጊዜ ፣ ሙሴ ፡ በኮሬብ ፡ካስቀመጣቸው ፡ ከሁለቱ ፡ የድንጋይ ፡ ጽላቶች ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ አልነበረበትም ። ፲ ካህናቱም ፡ ከመቅደሱ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ደመናው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፲፩ ቤት ፡ ሞላው ። የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ሞልቶ ፡ ነበርና ፡ ካህናቱ ፡ ከደመናው ፡ የተነሣ ፡ ለማገልገል ፡ ይቆሙ ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉም ።

፲፪ ሰሎሞንም ፦ እግዚአብሔር ፦ በጨለ ፲፫ ማው ፡ ውስጥ ፡ እኖራለሁ ፡ ብሎአል ፤ እኔም ፡ ለዘላለም ፡ የምትኖርበት ፡ ማደሪያ ፡ ቤት ፡ በእውነት ፡ ፲፬ ሠራሁልህ ፡ አለ ። ንጉሡም ፡ ፊቱን ፡ ዘወር ፡ አድርጎ ፡ የእስራኤልን ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ መረቀ ፤ የእስራኤልም ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ ቆመው ፡ ነበር ። ፲፭፡፲፮ እርሱም ፡ አለ ፦ ሕዝቤን ፡ እስራኤልን ፡ ከግብጽ ፡ ካወጣሁበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ ስሜ ፡ በዚያ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፣ በእርስዋም ፡ ቤት ፡ ይሠራልኝ ፡ ዘንድ ፡ ከእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ ከተማ ፡ አልመረጥሁም ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ስሜ ፡ በዚያ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ መርጫለሁ ፣ በሕዝቤም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ዳዊትን ፡ መርጫለሁ ፡ ብሎ ፡ ለአባቴ ፡ ለዳዊት ፡ በአፉ ፡ የተናገረ ፣ በእጁም ፡ የፈጸመ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፲፯ ይመስገን ። አባቴም ፡ ዳዊት ፡ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ቤት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ በልቡ ፡ አሰበ ። ፲፰ እግዚአብሔርም ፡ አባቴን ፡ ዳዊትን ፦ ለስሜ ፡ ቤት ፡ ትሠራ ፡ ዘንድ ፡ በልብህ ፡ አስበሃልና ፡ ይህን ፡ በልብህ ፡ማሰብህ ፡ መልካም ፡ አደረግህ ። ፲፱ ነገር ፡ ግን ፡ ከወገብህ ፡ የሚወጣው ፡ ልጅህ ፡ እርሱ ፡ ለስሜ ፡ ቤት ፡ ይሠራል ፡ እንጂ ፡ ቤት ፡ የምትሠራልኝ ፡ አንተ ፡ አይደለህም ፡ አለው ። ፳ እግዚአብሔርም ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ አጸና ፤ እግዚአብሔርም ፡ ተስፋ ፡ እንደ ፡ ሰጠ ፡ በአባቴ ፡ በዳዊት ፡ ፋንታ ፡ ተነሣሁ ፣ በእስራኤልም ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ተቀመጥሁ ፣ ለእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ቤት ፡ ሠራሁ ። ፳፩ ከግብጽም ፡ ምድር ፡ በወጣቸው ፡ ጊዜ ፡ ከአባቶቻችን ፡ ጋር ፡ ያደረገው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ላለበት ፡ ታቦት ፡ ስፍራ ፡ በዚያ ፡ አደረግሁለት ።

፳፪ የእስራኤልም ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ እያዩ ፡ ሰሎሞን ፡ በእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ፊት ፡ ቆሞ ፡ እጆቹን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ዘረጋ ። ፳፫ እንዲህም ፡ አለ ፦ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ፣ በላይ ፡ በሰማይ ፡ በታችም ፡ በምድር ፡ አንተን ፡ የሚመስል ፡ አምላክ ፡ የለም ፤ በፍጹም ፡ ልባቸው ፡ በፊትህ ፡ ለሚሄዱ ፡ ባሪያዎችህ ፡ ቃል ፡ ኪዳንንና ፡ ምሕረትን ፡ የምትጠብቅ ፣ ፳፬ ለባሪያህ ፡ ለአባቴ ፡ ለዳዊት ፡ የሰጠኸውን ፡ ተስፋ ፡ የጠበቅህ ፤ በአፍህ ፡ ተናገርህ ፣ እንደ ፡ ዛሬው ፡ ቀንም ፡ በእጅህ ፡ ፈጸምኸው ። ፳፭ አሁንም ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ፦ አንተ ፡ በፊቴ ፡ እንደ ፡ ሄድህ ፡ ልጆችህ ፡ መንገዳቸውን ፡ ቢጠብቁ ፣ በእስራኤል ፡ ዙፋን ፡ የሚቀመጥ ፡ ሰው ፡ በፊቴ ፡ አታጣም ፡ ብለህ ፡ ተስፋ ፡ የሰጠኸውን ፡ ለአባቴ ፡ ለዳዊት ፡ ጠብቅ ። ፳፮ አሁንም ፣ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፣ ለባሪያህ ፡ ለአባቴ ፡ ለዳዊት ፡ የተናገርኸው ፡ ቃል ፣ እባክህ ፣ ይጽና ።

፳፯ በውኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሰው ፡ ጋር ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ይኖራልን ? እነሆ ፣ ሰማይ ፡ ከሰማያትም ፡ በላይ ፡ ያለው ፡ ሰማይ ፡ ይይዝህ ፡ ዘንድ ፡ አይችልም ፤ ይልቁንስ ፡ እኔ ፡ የሠራሁት ፡ ቤት ፡ እንዴት ፡ ያንስ ! ፳፰ ነገር ፡ ግን ፣ አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፣ ወደ ፡ ባሪያህ ፡ ጸሎትና ፡ ልመና ፡ ተመልከት ፣ ዛሬም ፡ ባሪያህ ፡ በፊትህ ፡ የሚጸልየውን ፡ ጸሎትና ፡ ጥሪውን ፡ ስማ ፤ ፳፱ ባሪያህ ፡ ወደ ፡ ዚህ ፡ ስፍራ ፡ የሚጸልየውን ፡ ጸሎት ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፦ በዚያ ፡ ስሜ ፡ ይሆናል ፡ ወዳልኸው ፡ ስፍራ ፡ ወደዚህ ፡ ቤት ፡ ዓይኖችህ ፡ ሌሊትና ፡ ቀን ፡ የተገለጡ ፡ ይሁኑ ። ፴ ባሪያህና ፡ ሕዝብህ ፡ እስራኤል ፡ ወደዚህ ፡ ስፍራ ፡ የሚጸልዩትን ፡ ልመና ፡ ስማ ፤ በማደሪያህ ፡ በሰማይ ፡ ስማ ፤ ሰምተህም ፡ ይቅር ፡ በል ።

፴፩ ሰው ፡ ባልንጀራውን ፡ ቢበድል ፣ በላዩም ፡ መሐላ ፡ ቢጫን ፣ እርሱም ፡ መጥቶ ፡ በዚህ ፡ ቤት ፡ በመሠዊያህ ፡ ፊት ፡ ቢምል ፣ ፴፪ በሰማይ ፡ ስማ ፡ አድርግም ፤ በባሪያዎችህም ፡ ላይ ፡ ዳኛ ፡ ሁን ፤ በበደለኛውም ፡ ላይ ፡ ፍረድ ፣ መንገዱ

ንም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ መልስበት ፤ ንጹሑን ፡ አጽ
ድቀው ፡ እንደ ፡ ጽድቁም ፡ ክፈለው ።
፴፫ ሕዝብህ ፡ እስራኤል ፡ አንተን ፡ ስለ ፡ በደሉ ፡
በጠላቶቻቸው ፡ ፊት ፡ ድል ፡ በተመቱ ፡ ጊዜ ፥
ወደ ፡ አንተ ፡ ቢመለሱ ፥ ስምህንም ፡ ቢያከብሩ ፥
፴፬ በዚህም ፡ ቤት ፡ ቢጸልዩና ፡ ቢለምኑህ ፥ አንተ ፡
በሰማይ ፡ ስማ ፤ የሕዝብህንም ፡ የእስራኤልን ፡
ኃጢአት ፡ ይቅር ፡ በል ፥ ለአባቶቻቸውም ፡ ወደ ፡
ሰጠሃት ፡ ምድር ፡ መልሳቸው ።
፴፭ አንተን ፡ ስለ ፡ በደሉ ፡ ሰማይ ፡ በተዘጋ ፡ ጊዜ ፡
ዝናብም ፡ በልዘነበ ፡ ጊዜ ፥ ወደዚህ ፡ ስፍራ ፡
ቢጸልዩ ፥ ስምህንም ፡ ቢያከብሩ ፥ በስጨነቅሃ
ቸውም ፡ ጊዜ ፡ ከኃጢአታቸው ፡ ቢመለሱ ፥
፴፮ አንተ ፡ በሰማይ ፡ ስማ ፤ የሚሄዱበትንም ፡ መል
ካም ፡ መንገድ ፡ በማሳየት ፡ የባሪያዎችህንና ፡ የሕ
ዝብህን ፡ የእስራኤልን ፡ ኃጢአት ፡ ይቅር ፡ በል ፤
ለሕዝብህም ፡ ርስት ፡ አድርገህ ፡ ለሰጠሃት ፡
ምድር ፡ ዝናብ ፡ ስጥ ።
፴፯ በምድር ፡ ላይ ፡ ራብ ፥ ወይም ፡ ቸነፈር ፥
ወይም ፡ ዋግ ፥ ወይም ፡ አረማሞ ፥ ወይም ፡ አን
በጣ ፥ ወይም ፡ ኵብኵብ ፡ ቢሆን ፥ የሕዝብህም ፡
ጠላት ፡ የአገሩን ፡ ቀበሌዎች ፡ ከብቦ ፡ ቢያስጨ
ንቃቸው ፥ መቅሠፍትና ፡ ደዌ ፡ ሁሉ ፡ ቢሆን ፥
፴፰ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ የልቡን ፡ ሕመም ፡ አውቆ ፡
ጸሎትና ፡ ልመና ፡ ቢጸልይ ፥ እጆቹንም ፡ ወደ
፴፱ ፵ ዚህ ፡ ቤት ፡ ቢዘረጋ ፥ ለአባቶቻችን ፡ በሰጠሃት ፡
ምድር ፡ ላይ ፡ በሚኖሩበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ይፈ
ሩህ ፡ ዘንድ ፡ በማደሪያህ ፡ በሰማይ ፡ ስማ ፥ ይቅ
ርም ፡ በል ፤ አንተ ፡ ብቻ ፡ የሰውን ፡ ልጆች ፡
ሁሉ ፡ ልብ ፡ ታውቃለህና ፡ ልቡን ፡ ለምታው
ቀው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ መንገዱ ፡ ሁሉ ፡
መጠን ፡ ክፈለውና ፡ ስጠው ።
፵፩ ፵፪ ከሕዝብህም ፡ ከእስራኤል ፡ ወገን ፡ ያልሆነ ፡
እንግዳ ፡ ታላቁን ፡ ስምህን ፥ ብርቱይቱንም ፡
እጅህን ፥ የተዘረጋውንም ፡ ክንድህን ፡ ሰምቶ ፡
ስለ ፡ ስምህ ፡ ከሩቅ ፡ አገር ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፥ መጥ
፵፫ ቶም ፡ ወደዚህ ፡ ቤት ፡ በጸለየ ፡ ጊዜ ፥ አንተ ፡
በማደሪያህ ፡ በሰማይ ፡ ስማ ፤ የምድርም ፡ አሕ
ዛብ ፡ ሁሉ ፡ ስምህን ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡
ሕዝብህም ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ ይፈሩህ ፡ ዘንድ ፥
በዚህም ፡ በሠራሁት ፡ ቤት ፡ ስምህ ፡ እንደ ፡
ተጠራ ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፥ እንግዳው ፡ የሚለም
ንህን ፡ ሁሉ ፡ አድርግ ።
፵፬ ሕዝብህም ፡ ጠላቶቻቸውን ፡ ለመውጋት ፡
አንተ ፡ በምትልካቸው ፡ መንገድ ፡ ቢወጡ ፥
አንተም ፡ ወደ ፡ መረጥሃት ፡ ከተማ ፡ እኔም ፡ ለስ
ምህ ፡ ወደ ፡ ሠራሁት ፡ ቤት ፡ ለእግዚአብሔር ፡
፵፭ ቢጸልዩ ፥ ጸሎታቸውንና ፡ ልመናቸውን ፡ በሰ
ማይ ፡ ስማ ፥ ፍርድንም ፡ አድርግላቸው ።
፵፮ የማይበድልም ፡ ሰው ፡ የለምና ፡ አንተን ፡
ቢበድሉ ፥ ተቈጥተህም ፡ ለጠላቶቻቸው ፡ አሳ
ልፈህ ፡ ብትሰጣቸው ፡ ሩቅ ፡ ወይም ፡ ቅርብ ፡
ወደ ፡ ሆነ ፡ ወደ ፡ ጠላቶች ፡ አገር ፡ ቢማረኩም ፥
፵፯ በተማረኩበትም ፡ አገር ፡ ሆነው ፡ በልባቸው ፡
ንስሐ ፡ ቢገቡ ፥ በማራኪዎቹም ፡ አገር ፡ ሳሉ ፡
ተመልሰው ፦ ኃጢአት ፡ ሠርተናል ፥ በድለ
ንማል ፥ ክፉንም ፡ አድርገናል ፡ ብለው ፡ ቢለም
፵፰ ኑህ ፥ በማረኩአቸው ፡ በጠላቶቻቸው ፡ አገር ፡
ሳሉ ፡ በፍጹም ፡ ልባቸውና ፡ በፍጹም ፡ ነፍ
ሳቸው ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ቢመለሱ ፥ ለአባቶቻ
ቸው ፡ ወደ ፡ ሰጠሃት ፡ ወደ ፡ ምድራቸው ፡
ወደ ፡ መረጥሃትም ፡ ከተማ ፡ ለስምህም ፡ ወደ ፡
፵፱ ሠራሁት ፡ ቤት ፡ ቢጸልዩ ፥ ጸሎታቸውንና ፡
ልመናቸውን ፡ በማደሪያህ ፡ በሰማይ ፡ ስማ ፥
፶ ፍርድንም ፡ አድርግላቸው ፥ አንተንም ፡ የበደ
ሉህን ፡ ሕዝብህን ፥ በአንተም ፡ ላይ ፡ ያደ
ረጉትን ፡ በደላቸውን ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡ በል ፤
ይራሩላቸውም ፡ ዘንድ ፡ በማረኩአቸው ፡ ፊት ፡
፶፩ ምሕረት ፡ ስጣቸው ፤ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ከብ
ረት ፡ እቶን ፡ ውስጥ ፡ ያወጣሃቸው ፡ ሕዝብህና ፡
፶፪ ርስትህ ፡ ናቸውና ። በጠሩህ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡
ትሰማቸው ፡ ዘንድ ፡ ለባሪያህና ፡ ለሕዝብህ ፡
ለእስራኤል ፡ ልመና ፡ ዓይኖችህ ፡ የተገለጡ ፡
፶፫ ይሁኑ ። ጌታዬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ አባቶ
ቻችንን ፡ ከግብጽ ፡ በወጣህ ፡ ጊዜ ፡ በባሪያህ ፡
በሙሴ ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ተናገርህ ፡ ርስት ፡ ይሆ
ኑህ ፡ ዘንድ ፡ ከምድር ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ለይተ
ሃቸዋልና ።
፶፬ ሰሎሞንም ፡ ይህችን ፡ ጸሎትና ፡ ልመና ፡
ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጸልዮ ፡ በፈጸመ ፡
ጊዜ ፥ በጕልበቱ ፡ ተንበርክኮ ፡ እጁንም ፡ ወደ ፡
ሰማይ ፡ ዘርግቶ ፡ ነበርና ፡ ከእግዚአብሔር ፡
፶፭ መሠዊያ ፡ ፊት ፡ ተነሣ ። ቆሞም ፡ የእስራኤ
ልን ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ሲመ
፶፮ ርቅ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ እንደ ፡ ተናገረው ፡
ተስፋ ፡ ሁሉ ፡ ለሕዝቡ ፡ ለእስራኤል ፡ ዕረፍትን ፡
የሰጠ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ፤ በባሪያው ፡
በሙሴ ፡ ከሰጠው ፡ ከመልካም ፡ ተስፋ ፡ ሁሉ ፡
፶፯ አንድ ፡ ቃል ፡ አልወደቀም ። አምላካችን ፡
እግዚአብሔር ፡ ከአባቶቻችን ፡ ጋር ፡ እንደ ፡
ነበረ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፤ አይተወን ፥ አይጣ
፶፰ ለንም ፤ በመንገዱም ፡ ሁሉ ፡ እንሄድ ፡ ዘንድ ፥
ለአባቶቻችንም ፡ ያዘዛትን ፡ ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡
ትእዛዙንም ፡ እንጠብቅ ፡ ዘንድ ፥ ልባችንን ፡
፶፱ ወደ ፡ እርሱ ፡ ያዘንብል ፡ ዘንድ ። ለባሪያውና ፡
ለሕዝቡ ፡ ለእስራኤል ፡ በየዕለቱ ፡ ፍርድን ፡
ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ይህች ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ የለመንኋት ፡ ቃል ፡ በቀንና ፡ በሌሊት ፡
ወደ ፡ አምላካችን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የቀረ
፷ በች ፡ ትሁን ፤ የምድር ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እርሱ ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ከእር
ሱም ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ እንደሌለ ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ።
፷፩ እንደ ፡ ዛሬው ፡ ቀን ፡ በሥርዓቱ ፡ ትሄዱ ፡ ዘንድ ፥
ትእዛዙንም ፡ ትጠብቁ ፡ ዘንድ ፥ ከአምላካችን ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ ልባችሁ ፡ ፍጹም ፡
ይሁን ።
፷፪ ንጉሡም ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዉ ።

፷፫ ሰሎሞንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይሠዋ ፡ ዘንድ ፡
ለደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ ሀያ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡
በሬዎችና ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሺህ ፡ በጎች ፡ አቀረበ ።
ንጉሡና ፡ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ እን
፷፬ ዲሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ቀደሱ ። በእ
ግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያለው ፡ የናሱ ፡ መሠዊያ ፡
የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የእህሉን ፡ ቁር
ባን ፡ የደኅንነቱንም ፡ መሥዋዕት ፡ ስብ ፡ ይይዝ ፡
ዘንድ ፡ ታናሽ ፡ ስለ ፡ ነበረ ÷ በዚያ ፡ የሚቃጠ
ለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የእህሉን ፡ ቁርባን ፡ የደ
ኅንነቱንም ፡ መሥዋዕት ፡ ስብ ፡ አሳርጎአልና ፡
በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ፊት ፡ የነበረውን ፡ የአ
ደባባዩ ፡ መካከል ፡ ንጉሡ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ቀደሰ ።
፷፭ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ሰሎሞን ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡
እስራኤል ፡ ሁሉ ÷ ከሐማት ፡ መግቢያ ፡ ጀምሮ ፡
እስከ ፡ ግብጽ ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ፡ ያለው ፡ ታላቅ ፡
ጉባኤ ÷ በአምላካችን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
፷፮ ሰባት ፡ ቀን ፡ በዓሉን ፡ አደረጉ ። በስምንተኛ
ውም ፡ ቀን ፡ ሕዝቡን ፡ አሰናበተ ፤ እነርሱም ፡
ንጉሡን ፡ መረቁ ÷ እግዚአብሔርም ፡ ለባሪ
ያው ፡ ለዳዊትና ፡ ለሕዝቡ ፡ ለእስራኤል ፡ ስላ
ደረገው ፡ ቸርነት ፡ ሁሉ ፡ በልባቸው ፡ ተደስ
ተው ፡ ሐሤትም ፡ አድርገው ፡ ወደ ፡ ስፍራ
ቸው ፡ ሄዱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ሰሎሞንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ÷ የንጉ
ሡን ፡ ቤትና ፡ ሰሎሞን ፡ የወደደውን ፡ የል
ቡን ፡ አሳብ ፡ ሁሉ ፡ ሠርቶ ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ÷
፪ እግዚአብሔር ፡ በገባዖን ፡ ለሰሎሞን ፡ እንደ ፡
፫ ተገለጠለት ፡ ዳግመኛ ፡ ተገለጠለት ። እግዚአ
ብሔርም ፡ አለው ፡— በፊቴ ፡ የጸለይኸውን ፡
ጸሎትህንና ፡ ልመናህን ፡ ሰምቻለሁ ፤ ለዘላለ
ምም ፡ ስሜ ፡ በዚያ ፡ ያድር ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡ የሠ
ራኸውን ፡ ቤት ፡ ቀድሻለሁ ፤ ዓይኖቼና ፡ ልቤም ፡
፬ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ በዚያ ፡ ይሆናሉ ። ዳዊትም ፡
አባትህ ፡ በየዋህ ፡ ልብና ፡ በቅንነት ፡ እንደ ፡
ሄደ ፡ አንተ ፡ ደግሞ ፡ በፊቴ ፡ ብትሄድ ÷ ያዘዝ
ሁህንም ፡ ሁሉ ፡ ብታደርግ ÷ ሥርዓቴንም ፡ ፍር
፭ ዴንም ፡ ብትጠብቅ ÷ እኔ ፡— ከእስራኤል ፡
ዙፋን ፡ ከዘርህ ፡ ሰው ፡ አታጣም ፡ ብዬ ፡ ለአባ
ትህ ፡ ለዳዊት ፡ እንደ ፡ ተናገርሁ ÷ የመንግሥ
ትህን ፡ ዙፋን ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ለዘላለም ፡
፮ አጸናለሁ ። እናንተና ፡ ልጆቻችሁ ፡ ግን ፡ እኔን ፡
ከመከተል ፡ ብትመለሱ ÷ የሰጠኋችሁንም ፡ ትእ
ዛዜንና ፡ ሥርዓቴን ፡ ባትጠብቁ ÷ ሄዳችሁም ፡
ሌሎችን ፡ አማልክት ፡ ብታመልኩ ÷ ብትሰግዱ
፯ ላቸውም ÷ እስራኤልን ፡ ከሰጠኋቸው ፡ ምድር ፡
አጠፋቸዋለሁ ፤ ለስሜም ፡ የቀደስሁትን ፡ ይህን ፡
ቤት ፡ ከፊቴ ፡ እጥለዋለሁ ፤ እስራኤልም ፡ በአ
ሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ ምሳሌና ፡ ተረት ፡ ይሆ
፰ ናሉ ። ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎ ፡ የነበረውም ፡ ይህ ፡
ቤት ፡ ባድማ ፡ ይሆናል ፤ በዚያም ፡ የሚያልፍ ፡
ሁሉ ፡ እያፍዋጨ ፡— እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡
አገርና ፡ በዚህ ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እንዲህ ፡ አደ
፱ ረገ ? ብሎ ፡ ይደነቃል ። መልሰውም ፡— ከግ
ብጽ ፡ ምድር ፡ አባቶቻቸውን ፡ ያወጣውን ፡ አም
ላካቸውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትተው ፡ ሌሎችን ፡
አማልክት ፡ ስለ ፡ ተከተሉ ÷ ስለ ፡ ሰገዱላቸ
ውም ÷ ስለ ፡ አመለኩአቸውም ÷ ስለዚህ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አመጣባ
ቸው ፡ ይላሉ ።

፲ ሰሎሞንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤትና ፡ የን
ጉሡን ፡ ቤት ፡ ሁለቱን ፡ ቤቶች ፡ የሠራበት ፡
፲፩ ሀያ ፡ ዓመት ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ÷ ንጉሡ ፡ ሰሎ
ሞን ፡ በገሊላ ፡ ምድር ፡ ያሉትን ፡ ሀያ ፡ ከተ
ሞች ፡ ለኪራም ፡ ሰጠው ። የጢሮስም ፡ ንጉሥ ፡
ኪራም ፡ የሚሻውን ፡ ያህል ፡ የዝግባና ፡ የጥድ ፡
እንጨት ፡ የሚሻውንም ፡ ያህል ፡ ወርቅ ፡ ሁሉ ፡
፲፪ ለሰሎሞን ፡ ሰጥቶት ፡ ነበር ። ኪራምም ፡ ሰሎ
ሞን ፡ የሰጠውን ፡ ከተሞች ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ ከጢ
፲፫ ሮስ ፡ ወጣ ፤ ደስም ፡ አላሰኙትም ። እርሱም ፡—
ወንድሜ ፡ ሆይ ÷ የሰጠኸኝ ፡ እነዚህ ፡ ከተሞች ፡
ምንድር ፡ ናቸው ? አለ ። እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡
፲፬ የከቡል ፡ አገር ፡ ተብለው ፡ ተጠሩ ። ኪራምም ፡
መቶ ፡ ሀያ ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፡ ለንጉሡ ፡ ላከ ።
፲፭ ንጉሡም ፡ ሰሎሞን ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ቤትና ፡ የራሱን ፡ ቤት ÷ ሚሎንም ÷ የኢየሩሳ
ሌምንም ፡ ቅጥር ÷ ሐጸርንም ÷ መጊዶንም ÷
ጌዝርንም ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ገባሮችን ፡ መል
፲፮ ምሎ ፡ ነበር ። የግብጽም ፡ ንጉሥ ፡ ፈርዖን ፡
ወጥቶ ፡ ጌዝርን ፡ ይዞ ፡ ነበር ÷ በእሳትም ፡ አቃ
ጥሎ ፡ ነበር ÷ በከተማም ፡ የኖሩትን ፡ ከነዓና
ውያን ፡ ገድሎ ፡ ነበር ፤ ለልጁም ፡ ለሰሎሞን ፡
ሚስት ፡ ትሎት ፡ አድርጎ ፡ ሰጥቶአት ፡ ነበር ።
፲፯ ሰሎሞንም ፡ ጌዝርን ÷ የታችኛውንም ፡ ቤት
፲፰ ሖሮን ÷ ባዕላትንም ÷ በምድረ ፡ በዳም ፡ አገር ፡
፲፱ ያለችውን ፡ ተድሞርን ÷ ለሰሎሞንም ፡ የነበሩ
ትን ፡ የዕቃ ፡ ቤት ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ÷ የሰረገላ
ውንም ፡ ከተሞች ÷ የፈረሰኞችንም ፡ ከተሞች ÷
በኢየሩሳሌምም ፡ በሊባኖስም ፡ በመንግሥ
ቱም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ሰሎሞን ፡ ይሠራ ፡
፳ ዘንድ ፡ የወደደውን ፡ ሁሉ ፡ ሠራ ። ከእስራኤ
ልም ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ ያልነበሩትን ፡ ከአሞራ
ውያንና ፡ ከኬጢያውያን ÷ ከፌርዛውያን ÷ ከኤ
ዊያውያንና ፡ ከኢያቡሳውያን ፡ የቀሩትን ÷
፳፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ያጠፉአቸው ፡ ዘንድ ፡
ያልቻሉትን ÷ በኋላቸው ፡ የቀሩትን ፡ ልጆቻቸ
ውን ÷ ሰሎሞን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ገባሮች ፡
፳፪ አድርጎ ፡ መለመላቸው ። ሰሎሞንም ፡ ከእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ ማንንም ፡ ባሪያ ፡ አላደረገም ፤
እነርሱ ፡ ግን ፡ ሰልፈኞች ÷ ሎሌዎችም ÷ መሳ
ፍንትም ÷ አለቆችም ÷ የሰረገሎችና ፡ የፈረ
ሶች ፡ ባልደራሶች ፡ ነበሩ ።
፳፫ ሰሎሞንም ፡ በሚሠራው ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ ሠራ
ተኛውን ፡ ሕዝብ ፡ የሚያዝዙ ፡ አለቆች ፡ አም
ስት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ነበሩ ።
፳፬ የፈርዖንም ፡ ልጅ ፡ ከዳዊት ፡ ከተማ ፡ ሰሎ

ሞን፡ ወደ፡ ሠራላት፡ ወደ፡ ቤትዋ፡ ወጣች፤
በዚያን፡ ጊዜም፡ ሚሎን፡ ሠራ።
፳፭፤ ሰሎሞንም፡ በየዓመቱ፡ ሦስት፡ ጊዜ፡ የሚ
ቃጠለውንና፡ የደኅንነቱን፡ መሥዋዕት፡ ለእግ
ዚአብሔር፡ በሠራው፡ መሠዊያ፡ ላይ፡ ያሳርግ፡
ነበር፤ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ባለው፡ መሠ
ዊያ፡ ላይ፡ ዕጣን፡ ያሳርግ፡ ነበር፤ ቤቱንም፡
ጨረሰ።
፳፮፤ ንጉሡም፡ ሰሎሞን፡ በኤዶምያስ፡ ምድር፡
በኤርትራ፡ ባሕር፡ ዳር፡ በኤሎት፡ አጠገብ፡
ባለችው፡ በዔጽዮንጋብር፡ መርከቦችን፡ ሠራ።
፳፯፤ ኪራምም፡ በእነዚያ፡ መርከቦች፡ ከሰሎሞን፡
ባሪያዎች፡ ጋር፡ የባሕሩን፡ ነገር፡ የሚያውቁ፡
፳፰፤ መርከበኞች፡ ባሪያዎቹን፡ ሰደደ። ወደ፡ ኦፌ
ርም፡ መጡ ፥ ከዚያም፡ አራት፡ መቶ፡ ሀያ፡
መክሊተ፡ ወርቅ፡ ወሰዱ ፥ ወደ፡ ንጉሡም፡
ወደ፡ ሰሎሞን፡ ይዘው፡ መጡ።

## ምዕራፍ፡ ፲።

፩፡ የሳባም፡ ንግሥት፡ በእግዚአብሔር፡ ስም፡
የወጣለትን፡ የሰሎሞንን፡ ዝና፡ በሰማች፡ ጊዜ፡
በእንቆቅልሽ፡ ትፈትነው፡ ዘንድ፡ መጣች።
፪፤ በግመሎችም፡ ላይ፡ ሽቱና፡ እጅግ፡ ብዙ፡
ወርቅ፡ የከበረም፡ ዕንቍ፡ አስጭና፡ ከታላቅ፡
ጓዝ፡ ጋር፡ ወደ፡ ኢየሩሳሌም፡ ገባች፤ ወደ፡
ሰሎሞንም፡ በመጣች፡ ጊዜ፡ በልብዋ፡ ያለ
፫፤ ውን፡ ሁሉ፡ አጫወተችው። ሰሎሞንም፡
የጠየቀችውን፡ ሁሉ፡ ፈታላት፤ ሊፈታላት፡
ያልቻለውና፡ ከንጉሡ፡ የተሰወረ፡ ነገር፡
፬፤ አልነበረም። የሳባም፡ ንግሥት፡ የሰሎሞንን፡
ጥበብ፡ ሁሉ ፥ ሠርቶትም፡ የነበረውን፡ ቤት ፥
፭፤ የማዕዱንም፡ መብል ፥ የብላቴኖቹንም፡ አቀማ
መጥ ፥ የሎሌዎቹንም፡ አሠራር፡ አለባበሳቸው
ንም ፥ ጠጅ፡ አሳላፊዎቹንም ፥ በእግዚአብሔ
ርም፡ ቤት፡ የሚያሳርገውን፡ መሥዋዕት፡
፮፤ ባየች፡ ጊዜ፡ ነፍስ፡ አልቀረላትም። ንጉሡ
ንም፡ አለችው ፦ ስለ፡ ነገርህና፡ ስለ፡ ጥበብህ፡
በአገሬ፡ ሳለሁ፡ የሰማሁት፡ ዝና፡ እውነት፡ ነው።
፯፤ እኔም፡ መጥቼ፡ በዓይኔ፡ እስካይ፡ ድረስ፡ የነገ
ሩኝን፡ አላመንሁም፡ ነበር፤ እነሆም ፥ እኩሌታ
ውን፡ አልነገሩኝም፡ ነበር፤ ጥበብህና፡ ሥራህ፡
፰፤ ከሰማሁት፡ ዝና፡ ይበልጣል። በፊትህ፡ ሁል
ጊዜ፡ የሚቆሙ፡ ጥበብህንም፡ የሚሰሙ፡ ሰዎ
ችህና፡ እነዚህ፡ ባሪያዎችህ፡ ምስጉኖች፡
፱፤ ናቸው። አንተን፡ የወደደ ፥ በእስራኤልም፡
ዙፋን፡ ያስቀመጠህ፡ አምላክህ፡ እግዚአብ
ሔር፡ የተባረከ፡ ይሁን፤ እግዚአብሔር፡ እስራ
ኤልን፡ ለዘላለም፡ ወድዶታልና፡ ስለዚህ፡ ጽድ
ቅና፡ ፍርድ፡ ታደርግ፡ ዘንድ፡ ንጉሥ፡ አድ
፲፤ ርጎ፡ አስነሣህ። ለንጉሡም፡ መቶ፡ ሀያ፡ መክ
ሊት፡ ወርቅ፡ እጅግም፡ ብዙ፡ ሽቱ፡ የከበረም፡
ዕንቍ፡ ሰጠችው፤ የሳባ፡ ንግሥት፡ ለንጉሡ፡
ለሰሎሞን፡ እንደ፡ ሰጠችው፡ ያለ፡ የሽቱ፡
ብዛት፡ ከዚያ፡ ወዲያ፡ አልመጣም፡ ነበር።

፲፩፤ ከኦፊርም፡ ወርቅ፡ ያመጡ፡ የኪራም፡ መር
ከቦች፡ እጅግ፡ ብዙ፡ የሰንደል፡ እንጨትና፡
፲፪፤ የከበረ፡ ዕንቍ፡ ከኦፊር፡ አመጡ። ንጉሡም፡
ከሰንደሉ፡ እንጨት፡ ለእግዚአብሔር፡ ቤትና፡
ለንጉሡ፡ ቤት፡ መከታ ፥ ለመዘምራኑም፡ መሰ
ንቆና፡ በገና፡ አደረገ፤ እስከ፡ ዛሬም፡ ድረስ፡
እንደዚያ፡ ያለ፡ የሰንደል፡ እንጨት፡ ከቶ፡
አልመጣም፡ አልታየምም።
፲፫፤ ንጉሡም፡ ሰሎሞን ፥ በገዛ፡ እጁ፡ ከሰጣት፡
ሌላ ፥ የወደደችውን፡ ሁሉ፡ ከእርሱም፡ የለመ
ነችውን፡ ሁሉ፡ ለሳባ፡ ንግሥት፡ ሰጣት፤ እር
ስዋም፡ ተመልሳ፡ ከባሪያዎችዋ፡ ጋር፡ ወደ፡
ምድርዋ፡ ሄደች።
፲፬፡፲፭፤ ግብርም፡ የሚያስገብሩ፡ ሰዎች፡ ነጋዴዎ
ችም፡ የዓረብም፡ ነገሥታት፡ ሁሉ፡ የምድርም፡
ሹማምት፡ ከሚያወጡት፡ ሌላ ፥ በየዓመቱ፡ ለሰ
ሎሞን፡ የሚመጣለት፡ የወርቅ፡ ሚዛን፡ ስድ
ስት፡ መቶ፡ ስድሳ፡ ስድስት፡ መክሊት፡ ወርቅ፡
፲፮፤ ነበረ። ንጉሡም፡ ሰሎሞን፡ ከጥፍጥፍ፡ ወርቅ፡
ሁለት፡ መቶ፡ አላባሽ፡ አግሬ፡ ጋሻ፡ አሠራ፤
በአንዱም፡ አላባሽ፡ አግሬ፡ ጋሻ፡ ውስጥ፡ የገ
ባው፡ ወርቅ፡ ስድስት፡ መቶ፡ ሰቅል፡ ነበረ።
፲፯፤ ከጥፍጥፍም፡ ወርቅ፡ ሦስት፡ መቶ፡ ጋሻ፡
አሠራ፤ በአንዱም፡ ጋሻ፡ የገባው፡ ወርቅ፡
ሦስት፡ ምናን፡ ነበረ፤ ንጉሡም፡ የሊባኖስ፡
ዱር፡ በተባለው፡ ቤት፡ ውስጥ፡ አኖራቸው።
፲፰፤ ንጉሡም፡ ደግሞ፡ ከዝሆን፡ ጥርስ፡ ታላቅ፡
ዙፋን፡ አሠራ ፥ በጥሩም፡ ወርቅ፡ ለበጠው።
፲፱፤ ወደ፡ ዙፋንም፡ የሚያስኼዱ፡ ስድስት፡ እርከ
ኖች፡ ነበሩ፤ በስተ፡ ኋላውም፡ ያለው፡ የዙፋኑ፡
ራስ፡ ክብ፡ ነበረ፤ በዚህና፡ በዚያ፡ በመቀመ
ጫው፡ አጠገብ፡ ሁለት፡ የክንድ፡ መደገፊያ
ዎች፡ ነበሩበት ፥ በመደገፊያዎቹም፡ አጠገብ፡
፳፤ ሁለት፡ አንበሶች፡ ቆመው፡ ነበር። በስድስ
ቱም፡ እርከኖች፡ ላይ፡ በዚህና፡ በዚያ፡ አሥራ፡
ሁለት፡ አንበሶች፡ ቆመው፡ ነበር፤ በመንግሥ
ታት፡ ሁሉ፡ እንዲህ፡ ያለ፡ ሥራ፡ አልተሠ
፳፩፤ ራም። ንጉሡም፡ ሰሎሞን፡ የሚጠጣበት፡
ዕቃ፡ ሁሉ፡ ወርቅ፡ ነበረ ፥ የሊባኖስ፡ ዱር፡
የተባለውም፡ ቤት፡ ዕቃ፡ ሁሉ፡ ጥሩ፡ ወርቅ፡
እንጂ፡ ብር፡ አልነበረም። በሰሎሞን፡ ዘመን፡
፳፪፤ ብር፡ ከቶ፡ አይቈጠርም፡ ነበር። ለንጉሡም፡
ከኪራም፡ መርከቦች፡ ጋር፡ የተርሴስ፡ መርከ
ቦች፡ ነበሩት፤ በሦስት፡ በሦስት፡ ዓመትም፡
አንድ፡ ጊዜ፡ የተርሴስ፡ መርከቦች፡ ወርቅና፡
ብር ፥ የዝሆንም፡ ጥርስ ፥ ዝንጀሮና፡ ዝንጕር
ጕር፡ ወፍ፡ ይዘው፡ ይመጡ፡ ነበር።
፳፫፤ ንጉሡም፡ ሰሎሞን፡ በባለጠግነትና፡ በጥ
በብ፡ ከምድር፡ ነገሥታት፡ ሁሉ፡ በልጠ፡ ነበር።
፳፬፤ ምድርም፡ ሁሉ፡ እግዚአብሔር፡ በልቡ፡ ያኖ
ረለትን፡ ጥበቡን፡ ይሰማ፡ ዘንድ፡ የሰሎሞንን፡
፳፭፤ ፊት፡ ይመኝ፡ ነበር። ከእነርሱም፡ እያንዳንዱ፡
በዓመት፡ በዓመቱ፡ ገጸ፡ በረከቱን ፥ የብርና፡
የወርቅ፡ ዕቃ ፥ ልብስና፡ የጦር፡ መሣሪያ ፥

ሽቱም ÷ ፈረሶችና ፡ በቅሎች ፡ እየያዘ ፡ ይመጣ ፡ ነበር ።

፳፮ ሰሎሞንም ፡ ሰረገሎችንና ፡ ፈረሰኞችን ፡ ሰበሰበ ፤ አንድ ፡ ሺህ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሰረገሎች ÷ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህም ፡ ፈረሰኞች ፡ ነበሩት ÷ በሰረገሎችም ፡ ከተሞች ፡ ከንጉሡም ፡ ጋር ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አኖራቸው ። ፳፯ ንጉሡም ፡ ብሩን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ እንደ ፡ ድንጋይ ፡ እንዲበዛ ፡ አደረገው ፤ የዝግባም ፡ እንጨት ፡ ብዛት ፡ በቈላ ፡ እንደሚበቅል ፡ ሾላ ፡ ሆነ ። ፳፰ ሰሎሞንም ፡ ፈረሶችን ፡ ከግብጽና ፡ ከቀዌ ፡ አገር ፡ አስመጣ ፤ የንጉሡም ፡ ነጋዴዎች ፡ በገንዘብ ፡ እየገዙ ፡ ከቀዌ ፡ ያመጡአቸው ፡ ነበር ። ፳፱ አንዱም ፡ ሰረገላ ፡ በስድስት ፡ መቶ ÷ አንዱም ፡ ፈረስ ፡ በመቶ ፡ አምሳ ፡ ብር ፡ ከግብጽ ፡ ይወጣ ፡ ነበር ። እንዲሁም ፡ ለኬጢያውያንና ፡ ለሶርያ ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ በእጃቸው ፡ ያወጡላቸው ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ንጉሡም ፡ ሰሎሞን ፡ ከፈርዖን ፡ ልጅ ፡ ሌላ ÷ በሞዓባውያንና ፡ በአሞናውያን ፡ በኤዶማውያንም ፡ በሲዶናውያንና ፡ በኬጢያውያን ፡ ሴቶች ÷ በብዙ ፡ እንግዶች ፡ ሴቶች ፡ ፍቅር ፡ ተነደፈ ። ፪ እግዚአብሔር ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡— አምላኮቻቸውን ፡ ትከተሉ ፡ ዘንድ ፡ ልባችሁን ፡ በእውነት ፡ ያዘነብላሉና ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ አትግቡ ÷ እነርሱም ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ አይግቡ ፡ ካላቸው ፡ ከአሕዛብ ÷ ከእነዚህ ፡ ጋር ፡ ሰሎሞን ፡ በፍቅር ፡ ተጣበቀ ። ፫ ለእርሱም ፡ ወይዛዝር ፡ የሆኑ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሚስቶች ፡ ሦስት ፡ መቶም ፡ ቁባቶች ፡ ነበሩት ፤ ሚስቶቹም ፡ ልቡን ፡ አዘነበሉት ። ፬ ሰሎሞንም ፡ ሲሸመግል ፡ ሚስቶቹ ፡ ሌሎችን ፡ አማልክት ፡ ይከተል ፡ ዘንድ ፡ ልቡን ፡ አዘነበሉት ፤ የአባቱ ፡ የዳዊት ፡ ልብ ፡ ከአምላኩ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ ፍጹም ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ የሰሎሞን ፡ ልቡ ፡ እንዲሁ ፡ አልነበረም ። ፭ ሰሎሞንም ፡ የሲዶናውያንን ፡ አምላክ ፡ አስታሮትን ÷ የአሞናውያንንም ፡ ርኵሰት ፡ ሚልኮምን ፡ ተከተለ ። ፮ ሰሎሞንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ አደረገ ÷ እንደ ፡ አባቱም ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፡ እግዚአብሔርን ፡ በመከተል ፡ ፍጹም ፡ አልሆነም ። ፯ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሰሎሞን ፡ ለሞዓብ ፡ ርኵሰት ፡ ለካሞሽ ÷ ለአሞንም ፡ ልጆች ፡ ርኵሰት ፡ ለሞሎክ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ባለው ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ መስገጃ ፡ ሠራ ። ፰ ለአማልክቶቻቸው ፡ ዕጣን ፡ ለሚያጥኑ ፡ መሥዋዕትም ፡ ለሚሠዉ ፡ ለእንግዶች ፡ ሚስቶቹ ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ።

፱፡፲ ሁለት ፡ ጊዜም ፡ ከተገለጠለት ÷ ሌሎችንም ፡ አማልክት ፡ እንዳይከተል ፡ ካዘዘው ፡ ከእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ልቡን ፡ አርቆአልና ÷ እግዚአብሔርም ፡ ያዘዘውን ፡ ነገር ፡ አልጠበቀምና ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰሎሞንን ፡ ተቈጣ ። ፲፩ እግዚአብሔርም ፡ ሰሎሞንን ፡ አለው ፡— ይህን ፡ ሠርተሃልና ÷ ያዘዝሁህንም ፡ ቃል ፡ ኪዳኔንና ፡ ሥርዓቴን ፡ አልጠበቅህምና ፡ መንግሥትህን ፡ ከአንተ ፡ ቀዳድጄ ፡ ለባሪያህ ፡ እሰጠዋለሁ ። ፲፪ ነገር ፡ ግን ፡ ከልጅህ ፡ እጅ ፡ እቀድደዋለሁ ፡ እንጂ ፡ ስለ ፡ አባትህ ፡ ስለ ፡ ዳዊት ፡ ይህን ፡ በዘመንህ ፡ አላደርግም ። ፲፫ ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ባሪያዬ ፡ ስለ ፡ ዳዊትና ፡ ስለ ፡ መረጥኋት ፡ ስለ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ለልጅህ ፡ አንድ ፡ ነገድ ፡ እሰጣለሁ ፡ እንጂ ፡ መንግሥቱን ፡ ሁሉ ፡ አልቀድድም ።

፲፬ እግዚአብሔርም ፡ ከኤዶምያስ ፡ ነገሥታት ፡ ዘር ፡ የኤዶምያስን ፡ ሰው ፡ ሃዳድን ፡ ጠላት ፡ አድርጎ ፡ በሰሎሞን ፡ ላይ ፡ አስነሣው ። ፲፭፡፲፮ ኢዮአብና ፡ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ የኤዶምያስን ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ እስኪገድሉ ፡ ድረስ ፡ ስድስት ፡ ወር ፡ በዚያ ፡ ተቀምጠው ፡ ነበርና ፡ ዳዊት ፡ በኤዶምያስ ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ÷ የሠራዊቱም ፡ አለቃ ፡ ኢዮአብ ፡ ተወግተው ፡ የሞቱትን ፡ ሊቀብር ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ÷ የኤዶምያስንም ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ በገደለ ፡ ጊዜ ÷ ሃዳድ ፡ ገና ፡ ብላቴና ፡ ሳለ ፡ ሃዳድና ፡ ፲፯ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ጥቂቶቹ ፡ ከኤዶምያስ ፡ ሰዎች ፡ የሆኑ ፡ የአባቱ ፡ ባሪያዎች ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ኰብልለው ፡ ነበር ። ፲፰ ከምድያምም ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ ፋራን ፡ መጡ ፤ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ከፋራን ፡ ሰዎች ፡ ወሰዱ ÷ ወደ ፡ ግብጽም ፡ መጡ ÷ ወደ ፡ ግብጽም ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ፈርዖን ፡ ዘንድ ፡ ገቡ ፤ እርሱም ፡ ቤት ፡ ሰጥቶ ፡ ቀለብ ፡ ዳረገው ÷ ምድርም ፡ ሰጠው ። ፲፱ የሚስቱንም ፡ የእቴጌይቱን ፡ የቴቄምናስን ፡ እኅት ፡ እስኪያጋባው ፡ ድረስ ፡ ሃዳድ ፡ በፈርዖን ፡ ፊት ፡ እጅግ ፡ ባለሞዋል ፡ ሆነ ። ፳ የቴቄምናስ ፡ እኅት ፡ ጌንባትን ፡ ወለደችለት ÷ ቴቄምናስም ፡ በፈርዖን ፡ ቤት ፡ አሳደገችው ፤ ጌንባትም ፡ በፈርዖን ፡ ቤት ፡ በፈርዖን ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ነበረ ። ፳፩ ሃዳድም ፡ በግብጽ ፡ ሳለ ፡ ዳዊት ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ እንዳንቀላፋ ÷ የሠራዊቱም ፡ አለቃ ፡ ኢዮአብ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ÷ ሃዳድ ፡ ፈርዖንን ፡— ወደ ፡ አገሬ ፡ እሄድ ፡ ዘንድ ፡ አሰናብተኝ ፡ አለው ። ፳፪ ፈርዖንም ፡— እነሆ ÷ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ አገርህ ፡ መሄድ ፡ የፈለግህ ፡ ምን ፡ አጥተህ ፡ ነው ? አለው ። እርሱም ፡— አንዳች ፡ አላጣሁም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ልሂድ ፡ ብሎ ፡ መለሰ ። ሃዳድም ፡ ወደ ፡ አገሩ ፡ ተመለሰ ÷ ሃዳድም ፡ ያደረገው ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ እስራኤልን ፡ አስጨነቀ ÷ በኤዶምያስም ፡ ላይ ፡ ነገሠ ።

፳፫ እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፡ ከጌታው ፡ ከሱባ ፡ ንጉሥ ፡ ከአድርአዛር ፡ የኰበለለውን ፡ የኤልያዳን ፡ ልጅ ፡ ሬዞንን ፡ ጠላት ፡ አድርጎ ፡ አስነሣበት ። ፳፬ ዳዊትም ፡ የሱባን ፡ ሰዎች ፡ በገደለ ፡ ጊዜ ፡ ሬዞን ፡ ሰዎችን ፡ ሰብስቦ ፡ የጭፍራ ፡ አለቃ ፡ ሆነ ፤ ወደ ፡ ደማስቆም ፡ ሄዱ ÷ በዚያም ፡ ተቀመጡ ፤ በደማስቆም ፡ ላይ ፡ አነገሡት ። ፳፭ ሃዳድም ፡ ከደረገው ፡ ክፋት ፡ ሌላ ፡ በሰሎሞን ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ የእስራኤል ፡ ጠላት ፡ ነበረ ።

፳፮ ከሳሬራ ፡ አገር ፡ የሆነ ፡ የሰሎሞን ፡ ባሪያ ፡

የኤፍሬማዊው ፡ የናባጥ ፡ ልጅ ፡ ኢዮርብዓም ፡ በንጉሡ ፡ ላይ ፡ ዐመፀ ፤ እናቱም ፡ ጽሩዓ ፡ የተባለች ፡ በልቴት ፡ ሴት ፡ ነበረች ። ፳፯ በንጉሡም ፡ ያመፀበት ፡ ምክንያት ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ሰሎሞን ፡ ሚሎን ፡ ሠራ ፥ የአባቱንም ፡ የዳዊትን ፡ ከተማ ፡ ሰበራውን ፡ ጠገነ ። ፳፰ ኢዮርብዓምም ፡ ጽኑዕ ፡ ኃያል ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ሰሎሞንም ፡ ጕልማሳው ፡ በሥራ ፡ የተመሰገነ ፡ መሆኑን ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ በዮሴፍ ፡ ነገድ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሾመው ። ፳፱ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኢዮርብዓም ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ሴሎናዊው ፡ ነቢዩ ፡ አኪያ ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ ተገናኘው ፤ አኪያም ፡ አዲስ ፡ ልብስ ፡ ለብሶ ፡ ነበር ፡ ሁለቱም ፡ በሜዳው ፡ ለብቻቸው ፡ ነበሩ ። ፴ አኪያም ፡ የለበሰውን ፡ አዲስ ፡ ልብስ ፡ ይዞ ፡ ከአሥራ ፡ ሁለት ፡ ቄራረጠው ። ፴፩ ኢዮርብዓምንም ፡ አለው ፦ አሥር ፡ ቍራጭ ፡ ውሰድ ፤ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፦ እነሆ ፥ ከሰሎሞን ፡ እጅ ፡ መንግሥቱን ፡ እቀድዳለሁ ፥ አሥሩንም ፡ ነገዶች ፡ እሰጥሃለሁ ፤ ፴፪ ስለ ፡ ባሪያዬ ፡ ስለ ፡ ዳዊት ፡ ከእስራኤልም ፡ ነገድ ፡ ስለ ፡ መረጥኋት ፡ ከተማ ፡ ስለ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ነገድ ፡ ይቀርለታል ፤ ፴፫ ጥለውኛልና ፥ ለሲዶናውያንም ፡ አምላክ ፡ ለአስታሮት ፥ ለሞዓብም ፡ አምላክ ፡ ለካሞሽ ፥ ለአሞንም ፡ ልጆች ፡ አምላክ ፡ ለሚልኮም ፡ ሰግደዋልና ፥ አባቱም ፡ ዳዊት ፡ እንዳደረገ ፡ በፊቴ ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፥ ሥርዓቴንና ፡ ፍርዴንም ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ በመንገዴ ፡ አልሄዱምና ። ፴፬ መንግሥቱንም ፡ ሁሉ ፡ ከእጁ ፡ አልወስድም ፤ ትእዛዜንና ፡ ሥርዓቴን ፡ ስለ ፡ ጠበቀው ፡ ስለ ፡ መረጥሁት ፡ ስለ ፡ ባሪያዬ ፡ ስለ ፡ ዳዊት ፡ ግን ፡ በዕድሜው ፡ ሁሉ ፡ አለቃ ፡ አደርገዋለሁ ። ፴፭ መንግሥቱንም ፡ ከልጁ ፡ እጅ ፡ እወስዳለሁ ፥ ለአንተም ፡ አሥሩን ፡ ነገድ ፡ እሰጥሃለሁ ። ፴፮ ስሜንም ፡ በዋርሁበት ፡ በዚያች ፡ በመረጥኋት ፡ ከተማ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለባሪያዬ ፡ ለዳዊት ፡ በፊቴ ፡ ሁልጊዜ ፡ መብራት ፡ ይሆንለት ፡ ዘንድ ፡ ለልጁ ፡ አንድ ፡ ነገድ ፡ እሰጠዋለሁ ። ፴፯ አንተንም ፡ እወስድሃለሁ ፥ ነፍስህም ፡ በወደደችው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ትነግሣለች ፥ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ትሆናለህ ። ፴፰ በሪያዬም ፡ ዳዊት ፡ እንዳደረገ ፥ ያዘዝሁህን ፡ ሁሉ ፡ ብትሰማ ፥ በመንገዴም ፡ ብትሄድ ፥ በፊቴም ፡ የቀናውን ፡ ብታደርግ ፥ ሥርዓቴንና ፡ ትእዛዜን ፡ ብትጠብቅ ፥ ከአንተ ፡ ጋር ፡ እሆናለሁ ፥ ለዳዊትም ፡ እንደ ፡ ሠራሁለት ፡ ጽኑ ፡ ቤት ፡ እሠራልሃለሁ ፥ እስራኤልንም ፡ ለአንተ ፡ እሰጥሃለሁ ። ፴፱ ስለዚህም ፡ የዳዊትን ፡ ዘር ፡ አስጨንቃለሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በዘመን ፡ ሁሉ ፡ አይደለም ። ፵ ሰሎሞንም ፡ ኢዮርብዓምን ፡ ሊገድለው ፡ ወደደ ፤ ኢዮርብዓምም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ኰበለለ ፥ ወደ ፡ ግብጽም ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ሺሻቅ ፡ መጣ ፥ ሰሎሞንም ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ በግብጽ ፡ ተቀመጠ ።

፵፩ የቀረውም ፡ የሰሎሞን ፡ ነገር ፥ ያደረገውም ፡ ሁሉ ፥ ጥበቡም ፥ እነሆ ፥ በሰሎሞን ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፎአል ። ፵፪ ሰሎሞንም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የነገሠበት ፡ ዘመን ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ነበረ ። ፵፫ ሰሎሞንም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በአባቱም ፡ በዳዊት ፡ ከተማ ፡ ተቀበረ ፤ ልጁም ፡ ሮብዓም ፡ በፋንታው ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ያነግሡት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ሴኬም ፡ መጥተው ፡ ነበርና ፡ ሮብዓም ፡ ወደ ፡ ሴኬም ፡ ሄደ ። ፪ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ የናባጥ ፡ ልጅ ፡ ኢዮርብዓም ፡ ይህን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፥ እርሱም ፡ ከንጉሡ ፡ ከሰሎሞን ፡ ፊት ፡ ኰብልሎ ፡ በግብጽ ፡ ተቀምጦ ፡ ነበርና ፥ በግብጽም ፡ ሳለ ፡ ልከው ፡ ጠርተውት ፡ ነበርና ፡ ፫ ኢዮርብዓምና ፡ የእስራኤል ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ መጥተው ፡ ለሮብዓም ፦ ፬ አባትህ ፡ ቀንበር ፡ አክብዶብን ፡ ነበር ፤ አሁንም ፡ አንተ ፡ ጽኑውን ፡ የአባትህን ፡ አገዛዝ ፥ በላያችንም ፡ የጫነውን ፡ የከበደውን ፡ ቀንበር ፡ አቃልልልን ፤ እኛም ፡ እንገዛልሃለን ፡ ብለው ፡ ተናገሩት ። ፭ እርሱም ፦ ሂዱ ፥ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ተመለሱ ፡ አላቸው ። ሕዝቡም ፡ ሄዱ ።

፮ ንጉሡም ፡ ሮብዓም ፦ ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ እመልስለት ፡ ዘንድ ፡ የምትመክሩኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብሎ ፡ አባቱ ፡ ሰሎሞን ፡ በሕይወቱ ፡ ሳለ ፡ በፊቱ ፡ ይቆሙ ፡ ከነበሩት ፡ ሽማግሌዎች ፡ ጋር ፡ ተማከረ ። ፯ እነርሱም ፦ ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ አሁን ፡ ባሪያ ፡ ብትሆን ፡ ብትገዛላቸውም ፥ መልሰህም ፡ በገርነት ፡ ብትናገራቸው ፥ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ ባሪያዎች ፡ ይሆኑልሃል ፡ ብለው ፡ ተናገሩት ። ፰ እርሱ ፡ ግን ፡ ሽማግሌዎች ፡ የመከሩትን ፡ ምክር ፡ ትቶ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ካደጉትና ፡ በፊቱ ፡ ይቆሙ ፡ ከነበሩት ፡ ብላቴኖች ፡ ጋር ፡ ተማከረ ። ፱ እርሱም ፦ አባትህ ፡ የጫነብንን ፡ ቀንበር ፡ አቃልልልን ፡ ለሚሉኝ ፡ ሕዝብ ፡ እመልስላቸው ፡ ዘንድ ፡ የምትመክሩኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አላቸው ። ፲ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ያደጉት ፡ ብላቴኖች ፦ አባትህ ፡ ቀንበር ፡ አክብዶብናል ፥ አንተ ፡ ግን ፡ አቃልልልን ፡ ለሚሉህ ፡ ሕዝብ ፦ ታናሺቱ ፡ ጣቴ ፡ ከአባቴ ፡ ወገብ ፡ ትወፍራለች ። ፲፩ አሁንም ፡ አባቴ ፡ ከበድ ፡ ቀንበር ፡ ጭኖባችኋል ፥ እኔ ፡ ግን ፡ በቀንበራችሁ ፡ ላይ ፡ እጨምራለሁ ፤ አባቴ ፡ በአለንጋ ፡ ገርፎአችኋል ፥ እኔ ፡ ግን ፡ በጊንጥ ፡ እገርፋችኋለሁ ፡ በላቸው ፡ ብለው ፡ ተናገሩት ።

፲፪ ንጉሡም ፦ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ተመለሱ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ኢዮርብዓምና ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ሮብዓም ፡ መጡ ። ፲፫ ንጉሡም ፡ ሽማግሌዎች ፡ የመከሩትን ፡ ምክር ፡ ትቶ ፡ ለሕዝቡ ፡ ጽኑ ፡ ምላሽ ፡ መለሰላቸው ። ፲፬ እንደ ፡ ብላቴኖችም ፡

ምክር ፡— አባቴ ፡ ቀንበር ፡ አከብዶባችሁ ፡ ነበር ÷ እኔ ፡ ግን ፡ በቀንበራችሁ ፡ ላይ ፡ እጨምራለሁ ፤ አባቴ ፡ በአለንጋ ፡ ገርፎአችሁ ፡ ነበር ÷ እኔ ፡ ግን ፡ በጊንጥ ፡ እገርፋችኋለሁ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡፡ ፲፭ እግዚአብሔርም ፡ በሴሎናዊው ፡ በአኪያ ፡ አድርጎ ፡ ለናባጥ ፡ ልጅ ፡ ለኢዮርብዓም ፡ የተናገረውን ፡ ነገር ፡ እንዲያጸና ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ተመድቦ ፡ ነበርና ፡ ንጉሡ ፡ ሕዝቡን ፡ አልሰማም ፡፡

፲፮ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ንጉሡ ፡ እንዳልሰማቸው ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡ ፡ ለንጉሡ ፡— በዳዊት ፡ ዘንድ ፡ ምን ፡ ክፍል ፡ አለን ? በእሴይም ፡ ልጅ ፡ ዘንድ ፡ ርስት ፡ የለንም ፡፡ እስራኤል ፡ ሆይ ÷ ወደ ፡ ድንኳኖቻችሁ ፡ ተመለሱ ፤ ዳዊት ፡ ሆይ ÷ አሁን ፡ ቤትህን ፡ ተመልከት ፡ ብለው ፡ መለሱለት ፡፡ እስራኤልም ፡ ወደ ፡ ድንኳኖቻቸው ፡ ሄዱ ፡፡ ፲፯ በይሁዳ ፡ ከተሞች ፡ በተቀመጡት ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ግን ፡ ሮብዓም ፡ ነገሠባቸው ፡፡ ፲፰ ንጉሡም ፡ ሮብዓም ፡ አስገባሪውን ፡ አዶኒራምን ፡ ሰደደ ፤ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ በድንጋይ ፡ ደበደቡት ÷ ሞተም ፡፡ ንጉሡም ፡ ሮብዓም ፡ ፈጥኖ ፡ ወደ ፡ ሰረገላው ፡ ወጣ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ሸሸ ፡፡ ፲፱ እስራኤልም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ከዳዊት ፡ ቤት ፡ ሸፈተ ፡፡ ፳ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ኢዮርብዓም ፡ እንደ ፡ ተመለሰ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ልከው ፡ ወደ ፡ ሸንጎአቸው ፡ ጠሩት ÷ በእስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አነገሡት ፡፡ ከብቻው ፡ ከይሁዳ ፡ ነገድ ፡ በቀር ፡ የዳዊትን ፡ ቤት ፡ የተከተለ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ አልነበረም ፡፡

፳፩ ሮብዓምም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጣ ÷ የእስራኤልንም ፡ ቤት ፡ ወግተው ፡ መንግሥቱን ፡ ወደ ፡ ሰሎሞን ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ሮብዓም ፡ ይመልሱ ፡ ዘንድ ፡ ከይሁዳ ፡ ቤት ፡ ሁሉና ፡ ከብንያም ፡ ነገድ ፡ የተመረጡትን ፡ አንድ ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ ሺህ ፡ ሰልፈኞች ፡ ሰዎች ፡ ሰበሰበ ፡፡ ፳፪ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ሳማያ ፡— ፳፫ ለይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ለሰሎሞን ፡ ልጅ ፡ ለሮብዓምና ፡ ለይሁዳ ፡ ለብንያምም ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ፳፬ ለቀረውም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ይህ ፡ ነገር ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ነውና ፡ አትውጡ ÷ የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ ወንድሞቻችሁን ፡ አትውጉ ፤ እያንዳንዱም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ይመለስ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ፡ ሲል ፡ መጣ ፡፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ቃል ፡ ሰሙ ÷ እንደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ተመልሰው ፡ ሄዱ ፡፡

፳፭ ኢዮርብዓምም ፡ በተራራማው ፡ በኤፍሬም ፡ አገር ፡ ሴኬምን ፡ ሠርቶ ፡ በዚያ ፡ ተቀመጠ ፤ ደግሞም ፡ ከዚያ ፡ ወጥቶ ፡ ጵኒኤልን ፡ ሠራ ፡፡ ፳፮ ኢዮርብዓምም ፡ በልቡ ፡— አሁን ፡ መንግሥቱ ፡ ፳፯ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ቤት ፡ ይመለሳል ፡፡ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ መሥዋዕትን ፡ ያቀርብ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ቢወጣ ÷ የዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ልብ ፡ ወደ ፡ ጌታቸው ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ሮብዓም ፡ ይመለሳል ÷ እኔንም ፡ ይገድሉኛል ፡ አለ ፡፡ ፳፰ ንጉሡም ፡ ተማከረ ÷ ሁለትም ፡ የወርቅ ፡ ጥጆች ፡ አድርጎ ፡— እስራኤል ፡ ሆይ ÷ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ትወጡ ፡ ዘንድ ፡ ይበዛብችኋል ፤ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ያወጡህን ፡ አማልክቶችህን ፡ እይ ፡ አላቸው ፡፡ ፳፱ አንዱን ፡ በቤቴል ÷ ሁለተኛውንም ፡ በዳን ፡ አኖረ ፡፡ ፴ ለአንዱ ፡ ጥጃ ፡ ይሰግድ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝቡ ፡ እስከ ፡ ዳን ፡ ድረስ ፡ ይሄድ ፡ ነበርና ፡ ይህ ፡ ኃጢአት ፡ ሆነ ፡፡ ፴፩ በከረብቶቹም ፡ ላይ ፡ መስገጃዎች ፡ ሠራ ÷ ከሌዊ ፡ ልጆች ፡ ካይደሉ ፡ ከሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ካህናትን ፡ አደረገ ፡፡ ፴፪ በስምንተኛው ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ አምስተኛውም ፡ ቀን ፡ በይሁዳ ፡ እንደሚደረግ ፡ በዓል ፡ ያለ ፡ በዓል ፡ አደረገ ÷ በመሠዊያውም ፡ ላይ ፡ ሠዋ ፤ ለሠራቸውም ፡ ጥጆች ፡ ይሠዋ ፡ ዘንድ ፡ እንዲሁ ፡ በቤቴል ፡ አደረገ ፤ ለከረብታ ፡ መስገጃዎችም ፡ የመረጣቸውን ፡ ካህናት ፡ በቤቴል ፡ አኖራቸው ፡፡ ፴፫ በስምንተኛውም ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ አምስተኛው ፡ ቀን ፡ በልቡ ፡ ባሰበው ፡ ቀን ፡ በቤቴል ፡ በሠራው ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ ሠዋ ፤ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በዓል ፡ አደረገላቸው ፤ በመሠዊያውም ፡ ሠዋ ÷ ዕጣንም ፡ ዐጠነ ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ፡፡

፩ እነሆም ÷ አንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ከይሁዳ ፡ ወደ ፡ ቤቴል ፡ መጣ ፤ ኢዮርብዓምም ፡ ዕጣን ፡ እያጠነ ፡ በመሠዊያው ፡ አጠገብ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፡፡ ፪ በመሠዊያውም ፡ ላይ ፡— መሠዊያ ፡ ሆይ ÷ መሠዊያ ፡ ሆይ ÷ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ ስሙ ፡ ኢዮስያስ ፡ የሚባል ፡ ልጅ ፡ ለዳዊት ፡ ቤት ፡ ይወለዳል ፤ ዕጣንም ፡ የሚያጥኑብህን ፡ የከረብታ ፡ መስገጃዎቹን ፡ ካህናት ፡ ይሠዋብሃል ÷ የሰዎቹንም ፡ አጥንት ፡ ያቃጥልብሃል ፡ ብሎ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ጮኸ ፡፡ ፫ በዚያም ፡ ቀን ፡— እግዚአብሔር ፡ የተናገረው ፡ ምልክት ፡ ይህ ፡ ነው ፤ እነሆ ÷ መሠዊያው ፡ ይሰነጠቃል ÷ በላዩም ፡ ያለው ፡ አመድ ፡ ይፈስሳል ፡ ብሎ ፡ ምልክት ፡ ሰጠ ፡፡ ፬ ንጉሡም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ በቤቴል ፡ ባለው ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ የጮኸውን ፡ ነገር ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ÷ ኢዮርብዓም ፡ እጁን ፡ ከመሠዊያው ፡ አንሥቶ ፡— ያዙት ፡ አለ ፡፡ በእርሱም ፡ ላይ ፡ የዘረጋት ፡ እጅ ፡ ደረቀች ÷ ወደ ፡ እርሱም ፡ ይመልሳት ፡ ዘንድ ፡ አልተቻለውም ፡፡ ፭ የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንደ ፡ ሰጠው ፡ ምልክት ፡ መሠዊያው ፡ ተሰነጠቀ ÷ አመዱም ፡ ከመሠዊያው ፡ ፈሰሰ ፡፡ ፮ ንጉሡም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሰው ፡— አሁን ፡ የአምላክህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፊት ፡ ለምን ÷ እጄም ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ትመለስ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ ጸልይ ፡ አለው ፡፡ የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመነ ÷ የንጉሡም ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተመለሰች ÷ እንደ ፡ ቀድሞም ፡ ሆነች ፡፡

፯ ንጉሡም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሰው ፡— ከእኔ ፡
ጋር ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ ና ፡ እንጀራም ፡ ብላ ÷ በረከ
፰ ትም ፡ እሰጥሃለሁ ፡ አለው ። የእግዚአብሔ
ርም ፡ ሰው ፡ ንጉሡን ፡— የቤትህን ፡ እኩሌታ ፡
እንኳ ፡ ብትሰጠኝ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አልገባም ÷
በዚህም ፡ ስፍራ ፡ እንጀራ ፡ አልበላም ÷ ውኃም ፡
፱ አልጠጣም ፤ እንጀራ ፡ አትብላ ÷ ውኃም ፡ አት
ጠጣ ÷ በመጣህበትም ፡ መንገድ ፡ አትመለስ ፡
በሚል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ታዝዤአለሁና ፡
፲ አለው ። በሌላም ፡ መንገድ ፡ ሄደ ÷ ወደ ፡ ቤቴ
ልም ፡ በመጣበት ፡ መንገድ ፡ አልተመለሰም ።

፲፩ በቤቴልም ፡ አንድ ፡ ሽማግሌ ፡ ነቢይ ፡ ይቀ
መጥ ፡ ነበር ፤ ልጆቹም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጥ
ተው ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡
በቤቴል ፡ ያደረገውን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ነገሩት ፤
ደግሞም ፡ ለንጉሡ ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡
፲፪ ለአባታቸው ፡ ነገሩት ። አባታቸውም ፡— በማ
ናቸው ፡ መንገድ ፡ ሄደ ? አላቸው ። ልጆቹም ፡
ከይሁዳ ፡ የመጣው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡
፲፫ የሄደበትን ፡ መንገድ ፡ አመለከቱት ። ልጆቹ
ንም ፡— አህያውን ፡ ጫኑልኝ ፡ አላቸው ፤ አህ
ያውንም ፡ በጫኑለት ፡ ጊዜ ፡ ተቀመጠበት ።
፲፬ ከእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ በኋላ ፡ ሄደ ፤ በአድ
ባርም ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ ተቀምጦ ፡ አገኘውና ፡—
ከይሁዳ ፡ የመጣህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡
አንተ ፡ ነህን ? አለው ። እርሱም ፡— እኔ ፡ ነኝ ፡
፲፭ አለ ። እርሱም ፡— ከእኔ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡
፲፮ ና ÷ እንጀራም ፡ ብላ ፡ አለው ። እርሱም ፡—
ከአንተ ፡ ጋር ፡ እመለስና ፡ እገባ ፡ ዘንድ ፡ አይቻ
ለኝም ፤ በዚህም ፡ ስፍራ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ እን
፲፯ ጀራ ፡ አልበላም ÷ ውኃም ፡ አልጠጣም ፤ በዚያ ፡
እንጀራ ፡ አትብላ ÷ ውኃም ፡ አትጠጣ ÷ በመጣ
ህበትም ፡ መንገድ ፡ አትመለስ ፡ በሚል ፡ በእግ
፲፰ ዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ተብሎልኛልና ፡ አለ ። እር
ሱም ፡— እኔ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ አንተ ፡ ነቢይ ፡
ነኝ ፤ መልአክም ፡— እንጀራ ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡
ውኃም ፡ ይጠጣ ፡ ዘንድ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡
ቤትህ ፡ መልሰው ፡ ብሎ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ ተናገረኝ ፡ አለው ። ዋሽቶም ፡ ተናገረው ።
፲፱ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ተመለሰ ÷ በቤቱም ፡ እንጀራ ፡
በላ ÷ ውኃም ፡ ጠጣ ።

፳ በማዕድም ፡ ተቀምጠው ፡ ሳሉ ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ መለሰው ፡ ነቢይ ፡ መጣ ፤
፳፩ ከይሁዳም ፡ ወደ ፡ መጣው ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ሰው ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— በእግዚአብሔር ፡ አፍ ፡ ላይ ፡ ዐምፀ
ሃልና ÷ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ያዘዘህን ፡
፳፪ ትእዛዝ ፡ አልጠበቅህምና ÷ ተመልሰህም ፡—
እንጀራ ፡ አትብላ ÷ ውኃም ፡ አትጠጣ ፡ ባለህ ፡
ስፍራ ፡ እንጀራ ፡ በልተሃልና ÷ ውኃም ፡
ጠጥተሃልና ፡ ሬሳህ ፡ ወደ ፡ አባቶችህ ፡ መቃ
፳፫ ብር ፡ አይደርስም ፡ ብሎ ፡ ጮኸ ። እንጀራም ፡
ከበላ ÷ ውኃም ፡ ከጠጣ ፡ በኋላ ፡ አህያውን ፡
፳፬ ጫነለት ። ተመልሶም ፡ በሄደ ፡ ጊዜ ፡ በመን
ገዱ ፡ ላይ ፡ አንበሳ ፡ አግኝቶ ፡ ገደለው ፤ ሬሳ
ውም ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ ተጋድሞ ፡ ነበር ÷ አህ
ያውም ፡ በእርሱ ፡ አጠገብ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፤ አን
በሳውም ፡ ደግሞ ፡ በሬሳው ፡ አጠገብ ፡ ቆሞ ፡
፳፭ ነበር ። እነሆም ÷ መንገድ ፡ አላፊ ፡ ሰዎች ፡
ሬሳው ፡ በመንገዱ ፡ ወድቆ ፡ አንበሳውም ፡ በሬ
ሳው ፡ አጠገብ ፡ ቆሞ ፡ አዩ ፤ መጥተውም ፡
ሽማግሌው ፡ ነቢይ ፡ ተቀምጦበት ፡ በነበረው ፡
ከተማ ፡ አወሩ ።

፳፮ ያም ፡ ከመንገድ ፡ የመለሰው ፡ ነቢይ ፡ ያን ፡
በሰማ ፡ ጊዜ ፡— በእግዚአብሔር ፡ አፍ ፡ ላይ ፡
ያመፀ ፡ ያ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ነው ፤ እግ
ዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ ቃል ÷ እግዚ
አብሔር ፡ ለአንበሳ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶታል ፤
፳፯ ሰብሮም ፡ ገድሎታል ፡ አለ ። ልጆቹንም ፡—
አህያ ፡ ጫኑልኝ ፡ አላቸው ፤ እነርሱም ፡ ጫኑ
፳፰ ለት ። ሄደም ÷ ሬሳውም ፡ በመንገድ ፡ ወድቆ ÷
በሬሳውም ፡ አጠገብ ፡ አህያውና ፡ አንበሳው ፡
ቆመው ÷ አንበሳው ፡ ሬሳውን ፡ ሳይበላው ÷
፳፱ አህያውንም ፡ ሳይሰብረው ፡ አገኘ ። ነቢዩም ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ሰው ፡ ሬሳ ፡ አነሣ ÷ በአህ
ያውም ፡ ላይ ፡ ጭኖ ፡ መለሰው ፤ ያለቅስለትና ፡
ይቀብረው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ገዛ ፡ ከተማው ፡ ይዞት ፡
፴ መጣ ። ሬሳውንም ፡ በገዛ ፡ መቃብሩ ፡ አኖረው ፤
ዋይ ፡ ዋይ ፡ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ እያሉ ፡ አለቀ
፴፩ ሱለት ። ከቀበረውም ፡ በኋላ ፡ ልጆቹን ፡ እን
ዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— በሞትሁ ፡ ጊዜ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ በተቀበረበት ፡ መቃብር ፡
ቅበሩኝ ፤ አጥንቶቼንም ፡ በአጥንቶቹ ፡ አጠ
፴፪ ገብ ፡ አኑሩ ፤ በቤቴል ፡ ባለው ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ÷
በሰማርያም ፡ ከተሞች ፡ ውስጥ ፡ ባሉ ፡ በኮረብታ
ዎቹ ፡ መስገጃዎች ፡ ላይ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ የጮኸው ፡ ነገር ፡ በእውነት ፡ ይደርሳልና ።

፴፫ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ኢዮርብዓም ፡ ከክፉ ፡ መን
ገድ ፡ አልተመለሰም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ለኮረብታ
ዎቹ ፡ መስገጃዎች ፡ አብልጦ ፡ ከሕዝብ ፡ ሁሉ ፡
ካህናትን ፡ አደረገ ፤ የሚወድደውንም ፡ ሁሉ ፡ ይቀ
ድስ ፡ ነበር ÷ እርሱም ፡ ለኮረብታዎቹ ፡ መስገጃ
፴፬ ዎች ፡ ካህን ፡ ይሆን ፡ ነበር ። እስኪፈርስም ፡
ከምድርም ፡ እስኪጠፋ ፡ ድረስ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡
ለኢዮርብዓም ፡ ቤት ፡ ኃጢአት ፡ ሆነ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ በዚያም ፡ ወራት ፡ የኢዮርብዓም ፡ ልጅ ፡
፪ አብያ ፡ ታመመ ። ኢዮርብዓምም ፡ ሚስቱን ፡—
ተነሺ ÷ የኢዮርብዓምም ፡ ሚስት ፡ እንደ ፡ ሆንሽ ፡
እንዳትታወቂ ፡ ልብስሽን ፡ ለውጪና ፡ ወደ ፡
ሴሎ ፡ ሂጂ ፤ እነሆ ÷ በዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ እን
ድነግሥ ፡ የነገረኝ ፡ ነቢዩ ፡ አኪያ ፡ በዚያ ፡ አለ ።
፫ በእጅሽም ፡ አሥር ፡ እንጀራና ፡ እንጎቻዎች ፡
አንድም ፡ ምንቸት ፡ ማር ፡ ይዘሽ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡
ሂጂ ፤ በልጁም ፡ የሚሆነውን ፡ ይነግርሻል ፡
፬ አላት ። የኢዮርብዓምም ፡ ሚስት ፡ እንዲሁ ፡ አደ
ረገች ÷ ተነሥታም ፡ ወደ ፡ ሴሎ ፡ ሄደች ፤ ወደ ፡

አኪያም፡ቤት፡መጣች ። አኪያም ፡ ስለ፡ መሸ
ምገሉ፡ዓይኖቹ፡ፈዝዘው፡ነበርና ፤ ማየት፡አል
፭፡ ቻለም ። እግዚአብሔርም፡አኪያን ፡— እነሆ ÷
ስለ ፡ ታመመው ፡ ልጅዋ ፡ ትጠይቅህ ፡ ዘንድ ፡
የኢዮርብዓም ፡ ሚስት ፡ ትመጣለች ፤ ሌላ ፡
ሴትም ፡ መስላ ፡ ተሰውራለችና ፡ በገባች ፡ ጊዜ ፡
እንዲህና ፡ እንዲህ ፡ በላት ፡ አለው ።
፮፡ እርስዋም ፡ በደጅ ፡ ስትገባ ፡ አኪያ ፡ የእግር
ዋን ፡ ኮቴ ፡ ሰማ ÷ እንዲህም ፡ አለ ፡— የኢዮር
ብዓም ፡ ሚስት ፡ ሆይ ÷ ግቢ ፤ ስለ ፡ ምንስ ፡ ሌላ ፡
ሴት ፡ መሰልሽ ? እኔም ፡ ብርቱ ፡ ወሬ ፡ ይገሮ ፡
፯፡ ተልኬልሻለሁ ። ሂጂ ÷ ለኢዮርብዓምም ፡ እን
ዲህ ፡ በዪው ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ከሕዝብ ፡ መካከል ፡
ለይቼ ፡ ከፍ ፡ አድርጌህ ፡ ነበር ÷ በሕዝቤም ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ አድርጌህ ፡ ነበር ÷
፰፡ ከዳዊትም ፡ ቤት ፡ መንግሥቱን ፡ ቀድጄ ፡ ሰጥ
ቼህ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በፍጹም ፡ ልቡ ፡ እንደ ፡
ተከተለኝ ÷ በፊቴም ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ ብቻ ፡ እንዳ
ደረገ ÷ ትእዛዜንም ፡ እንደ ፡ ጠበቀ ፡ እንደ ፡ ባሪ
፱፡ ያዬ ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፡ አልሆንህም ። ከአንተም ፡
አስቀድመው ፡ ከነበሩት ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ክፉ ፡
ሠራህ ፤ ታስቈጣኝም ፡ ዘንድ ፡ ሄደህ ፡ ሌሎችን ፡
አማልክትና ፡ ቀልጠው ፡ የተሠሩትን ፡ ምስሎች ፡
፲፡ አደረግህ ÷ ወደ ፡ ኋላህም ፡ ጣልኸኝ ። ስለዚህ ÷
እነሆ ÷ በኢዮርብዓም ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ መከራ ፡
አመጣለሁ ÷ ከኢዮርብዓምም ፡ በእስራኤል ፡
ዘንድ ፡ የታሰረውንና ፡ የተለቀቀውን ፡ ወንድ ፡
ሁሉ ፡ እቈርጣለሁ ፤ ሰውም ፡ ፋንድያን ፡ እስኪ
ጠፋ ፡ ድረስ ፡ እንደሚጠርግ ፡ እኔ ፡ የኢዮርብ
፲፩፡ ዓምን ፡ ቤት ፡ ፈጽሜ ፡ እጠርጋለሁ ። ከኢዮ
ርብዓምም ፡ ወገን ፡ በከተማይቱ ፡ ውስጥ ፡ የሞ
ተውን ፡ ውሾች ፡ ይበሉታል ፤ በሜዳውም ፡
የሞተውን ፡ የሰማይ ፡ ወፎች ፡ ይበሉታል ፤
፲፪፡ እግዚአብሔር ፡ ተናግሮአልና ። እንግዲህ ፡ ተነ
ሥተሽ ፡ ወደ ፡ ቤትሽ ፡ ሂጂ ፤ እግርሽም ፡ ወደ ፡
፲፫፡ ከተማ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ልጁ ፡ ይሞታል ። እስራ
ኤልም ፡ ሁሉ ፡ ያለቅሱለታል ÷ ይቀብሩትማል ፤
በእስራኤል ፡ አምላክ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
በኢዮርብዓም ፡ ቤት ፡ በዚህ ፡ ልጅ ፡ መልካም ፡
ነገር ፡ ተገኝቶበታልና ፡ ከኢዮርብዓም ፡ እርሱ ፡
፲፬፡ ብቻ ፡ ይቀበራል ። እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ያስነሣል ፤ እርሱም ፡
በዚያ ፡ ዘመን ፡ የኢዮርብዓምን ፡ ቤት ፡ ያጠፋል ።
፲፭፡ በዚያ ፡ ጊዜም ፡ ሸምበቆ ፡ በውኃ ፡ ውስጥ ፡ እን
ደሚንቀሳቀስ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲሁ ፡ እስ
ራኤልን ፡ ይመታል ፤ እግዚአብሔርንም ፡ ያስ
ቈጡ ፡ ዘንድ ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀድ ፡ ተክለዋ
ልና ፡ ለአባቶቻቸው ፡ ከሰጣቸው ፡ ከዚች ፡ ከመ
ልካሚቱ ፡ ምድር ፡ እስራኤልን ፡ ይነቅላል ÷
፲፮፡ በወንዙም ፡ ማዶ ፡ ይበትናቸዋል ። ስለ ፡ በደ
ለውና ፡ እስራኤልንም ፡ ስላሳተበት ፡ ስለ ፡ ኢዮ
ርብዓም ፡ ኃጢአት ፡ እስራኤልን ፡ ይጥላል ።
፲፯፡ የኢዮርብዓምም ፡ ሚስት ፡ ተነሥታ ፡ ሄደች ÷
ወደ ፡ ቴርሳ ፡ መጣች ፤ ወደ ፡ ቤቱም ፡ መድ
፲፰፡ ረክ ፡ በገባች ፡ ጊዜ ፡ ልጁ ፡ ሞተ ። በባሪያውም ፡
በነቢዩ ፡ በአኪያ ፡ እንደ ፡ ተነገረው ፡ እንደ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ቀበሩት ፡
አለቀሱለትም ።
፲፱፡ የቀረውም ፡ የኢዮርብዓም ፡ ነገር ÷ እንዴት ፡
እንደ ፡ ተዋጋ ÷ እንዴትም ፡ እንደ ፡ ነገሠ ÷
እነሆ ÷ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽ
፳፡ ሐፍ ፡ ተጽፎአል ። ኢዮርብዓምም ፡ የነገሠ
በት ፡ ዘመን ፡ ሀያ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ነበረ ፤ ከአባ
ቶቹም ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ÷ ልጁም ፡ ናዳብ ፡ በፋ
ንታው ፡ ነገሠ ።
፳፩፡ የሰሎሞንም ፡ ልጅ ፡ ሮብዓም ፡ በይሁዳ ፡ ነገሠ ፤
ሮብዓምም ፡ ንጉሥ ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ የአርባ ፡
አንድ ፡ ዓመት ፡ ጐልማሳ ፡ ነበረ ፤ እግዚአብሔ
ርም ፡ ስሙን ፡ ያኖርባት ፡ ዘንድ ፡ ከእስራኤል ፡
ነገድ ፡ ሁሉ ፡ በመረጣት ፡ ከተማ ፡ በኢየሩሳ
ሌም ፡ አሥራ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ የእና
ቱም ፡ ስም ፡ ናዕማ ፡ ነበረ ፤ እርስዋም ፡ አሞና
፳፪፡ ዊት ፡ ነበረች ። ይሁዳም ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ክፉ ፡ ሠራ ፤ አባቶቻቸውም ፡ ከሠሩት ፡
ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ አብዝተው ፡ በሠሩት ፡ ኃጢአት ፡
፳፫፡ አስቈጡት ። እነርሱም ፡ ደግሞ ፡ ከፍ ፡ ባለው ፡
ኮረብታ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ÷ ቅጠሉ ፡ ከለመለመ ፡ ዛፍ ፡
ሁሉ ፡ በታች ፡ መስገጃዎችንና ፡ ሐውልቶችን ፡
የማምለኪያ ፡ ዐፀዶችንም ፡ ለራሳቸው ፡ ሠሩ ።
፳፬፡ በምድርም ፡ ውስጥ ፡ ሰዶማውያን ፡ ነበሩ ፤ ከእ
ስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ እግዚአብሔር ፡ ያሳ
ደዳቸውን ፡ የአሕዛብን ፡ ርኵሰት ፡ ሁሉ ፡ ያደ
ርጉ ፡ ነበር ።
፳፭፡ ሮብዓምም ፡ በነገሠ ፡ በአምስተኛው ፡ ዓመት ፡
የግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ሺሻቅ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡
፳፮፡ መጣ ። የእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ መዛግብት
ንና ፡ የንጉሥ ፡ ቤት ፡ መዛግብትን ፡ ወሰደ ፤
ሁሉንም ፡ ወሰደ ፤ ሰሎሞንም ፡ የሠራውን ፡
፳፯፡ የወርቁን ፡ ጋሻ ፡ ሁሉ ፡ ወሰደ ። ንጉሡም ፡ ሮብ
ዓም ፡ በፋንታው ፡ የናስ ፡ ጋሾችን ፡ ሠራ ÷ የን
ጉሥንም ፡ ቤት ፡ ደጅ ፡ በሚጠብቁ ፡ በዘበኞች ፡
፳፰፡ አለቆች ፡ እጅ ፡ አኖራቸው ። ንጉሡም ፡ ዘወ
ትር ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ሲገባ ፡ ዘበ
ኞች ፡ ይሸከሙአቸው ፡ ነበር ፤ መልሰውም ፡
በዘበኞች ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ያኖሩአቸው ፡ ነበር ።
፳፱፡ የቀረውም ፡ የሮብዓም ፡ ነገር ÷ ያደረገውም ፡
ሁሉ ÷ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡
፴፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? በዘመኑም ፡ ሁሉ ፡ በሮ
ብዓምና ፡ በኢዮርብዓም ፡ መካከል ፡ ሰልፍ ፡
፴፩፡ ነበረ ። ሮብዓምም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ÷
በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ተቀበረ ።
ልጁም ፡ አብያም ፡ በፋንታው ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩፡ የናባጥ ፡ ልጅ ፡ ኢዮርብዓም ፡ በነገሠ ፡ በአ
ሥራ ፡ ስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ አብያም ፡ በይ
፪፡ ሁዳ ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ሆነ ። በኢየሩሳሌምም ፡

ሦስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡ መዓካ ፡ የተ
፪ ባለች ፡ የአቤሴሎም ፡ ልጅ ፡ ነበረች ። ከእርሱ ፡
አስቀድሞ ፡ ባደረገው ፡ በአባቱ ፡ ኃጢአት ፡
ሁሉ ፡ ሄደ ፤ ልቡም ፡ እንደ ፡ አባቱ ፡ እንደ ፡
ዳዊት ፡ ልብ ፡ ከአምላኩ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
፬ ጋር ፡ ፍጹም ፡ አልነበረም ። ነገር ፡ ግን ፡ ልጁን ፡
ከእርሱ ፡ በኋላ ፡ ያስነሣ ፡ ዘንድ ፥ ኢየሩሳሌ
ምንም ፡ ያጸና ፡ ዘንድ ፡ አምላኩ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ስለ ፡ ዳዊት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ መብራት ፡
፭ ሰጠው ፤ ዳዊት ፡ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አድርጎ ፡ ነበርና ፥
ካዘዘውም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ፈቀቅ ፡ አላለም ፡ ነበ
፮ ርና ። በኢዮርብዓምና ፡ በሮብዓም ፡ ልጅ ፡ በአ
ብያም ፡ መካከል ፡ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ ጠብ ፡ ነበረ ።
፯ የቀረውም ፡ የአብያም ፡ ነገር ፥ ያደረገውም ፡
ሁሉ ፥ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡
የተጻፈ ፡ አይደለምን ? በአብያምና ፡ በኢዮር
፰ ብዓምም ፡ መካከል ፡ ሰልፍ ፡ ነበረ ። አብያምም ፡
ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡
ቀበሩት ። ልጁም ፡ አሳ ፡ በፋንታው ፡ ነገሠ ።
፱ በእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮርብዓም ፡ በሀ
ያኛው ፡ ዓመት ፡ አሳ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ነገሠ ።
፲ በኢየሩሳሌምም ፡ አርባ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤
እናቱም ፡ መዓካ ፡ የተባለች ፡ የአቤሴሎም ፡
፲፩ ልጅ ፡ ነበረች ። አሳ ፡ እንደ ፡ አባቱ ፡ እንደ ፡
ዳዊት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡
፲፪ አደረገ ። ከአገሩም ፡ ሰዶማውያንን ፡ አስወገደ ፥
አባቶቹም ፡ ያደረጉትን ፡ ጣዖታትን ፡ ሁሉ ፡
፲፫ አራቀ ። በማምለኪያ ፡ ዐፀድ ፡ ጣዖት ፡ ስላ
ሠራች ፡ እናቱን ፡ መዓካን ፡ እቴጌ ፡ እንዳት
ሆን ፡ ሻራት ፤ ጣዖትዋንም ፡ ሰበረው ፥ በቄድ
፲፬ ሮንም ፡ ፈፋ ፡ አጠገብ ፡ አቃጠለው ። ነገር ፡
ግን ፡ በኮረብቶች ፡ ላይ ፡ ያሉትን ፡ መስገጃዎች ፡
አላራቀም ፤ የአሳ ፡ ልብ ፡ ግን ፡ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡
፲፭ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ ፍጹም ፡ ነበረ ። አባቱ ፡
የቀደሰውንና ፡ እርሱም ፡ የቀደሰውን ፡ ወርቅና ፡
ብር ፡ ዕቃውንም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
አገባው ።

፲፮ በአሳና ፡ በእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ በባኦስ ፡
መካከል ፡ በዘመናቸው ፡ ሁሉ ፡ ሰልፍ ፡ ነበረ ።
፲፯ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ባኦስ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡
ወጣ ፤ ከይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ከአሳ ፡ ዘንድ ፡ ማንም ፡
እንዳይወጣ ፡ ወደ ፡ እርሱም ፡ ማንም ፡ እንዳይ
፲፰ ገባ ፡ አድርጎ ፡ ራማን ፡ ሠራ ። አሳም ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ ቤትና ፡ በንጉሥ ፡ ቤት ፡ መዛግብት ፡
የቀረውን ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ ሁሉ ፡ ወስዶ ፡ በባ
ሪያዎቹ ፡ እጅ ፡ ሰጣቸው ፤ ንጉሡም ፡ አሳ ፡ በደ
ማስቆ ፡ ለተቀመጠው ፡ ለአዚን ፡ ልጅ ፡ ለጠ
ብሪሞን ፡ ልጅ ፡ ለሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ ለወልደ ፡
፲፱ አዴር ፦ በእኔና ፡ በአንተ ፡ መካከል ፡ በአባ
ቴና ፡ በአባትህም ፡ መካከል ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
ጸንቶአል ፤ እነሆ ፥ ብርና ፡ ወርቅ ፡ ገጸ ፡ በረ
ከት ፡ ሰድጃልሃለሁ ፤ እርሱ ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡
እንዲርቅ ፡ ሄደህ ፡ ከእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ከባ
ኦስ ፡ ጋር ፡ ያለህን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አፍርስ ፡
፳ ብሎ ፡ ሰደደ ። ወልደ ፡ አዴርም ፡ ለንጉሡ ፡
ለአሳ ፡ እሺ ፡ አለው ፤ የሠራዊቱንም ፡ አለቆች ፡
በእስራኤል ፡ ከተሞች ፡ ላይ ፡ ሰድዶ ፡ ዒዮን
ንና ፡ ዳንን ፥ አቤልቤትመዓካንና ፡ ኪኔሬትን ፡
ሁሉ ፡ የንፍታሌምንም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ መታ ።
፳፩ ባኦስም ፡ ያን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ራማን ፡ መሥ
፳፪ ራት ፡ ትቶ ፡ በቴርሳ ፡ ተቀመጠ ። ንጉሡም ፡
አሳ ፡ በይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አዋጅ ፡ ነገረ ፤
ማንም ፡ ነጻ ፡ አልነበረም ፤ ባኦስም ፡ የሠራበ
ትን ፡ የራማን ፡ ድንጋይና ፡ እንጨት ፡ ወሰዱ ፥
ንጉሡም ፡ አሳ ፡ የብንያምን ፡ ጌባንና ፡ ምጽጳን ፡
ሠራበት ።

፳፫ የቀረውም ፡ የአሳ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፥ ጭከናውም ፡
ሁሉ ፥ ያደረገውም ፡ ሁሉ ፥ የሠራቸውም ፡ ከተ
ሞች ፥ በይሁዳ ፡ ነገሥት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡
የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ነገር ፡ ግን ፡ በሸመገለ ፡
፳፬ ጊዜ ፡ እግሮቹ ፡ ታመሙ ። አሳም ፡ ከአባቶቹ ፡
ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በአባቱም ፡ በዳዊት ፡ ከተማ ፡
ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ተቀበረ ። ልጁም ፡ ኢዮሣ
ፍጥ ፡ በፋንታው ፡ ነገሠ ።

፳፭ በይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ በአሳ ፡ በሁለተኛው ፡
ዓመት ፡ የኢዮርብዓም ፡ ልጅ ፡ ናዳብ ፡ በእስራ
ኤል ፡ ላይ ፡ ነገሠ ፤ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ሁለት ፡
፳፮ ዓመት ፡ ነገሠ ። በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡
አደረገ ፥ በአባቱም ፡ መንገድ ፡ እስራኤልንም ፡
፳፯ ባሳተበት ፡ ኃጢአት ፡ ሄደ ። ከይሳኮርም ፡ ቤት ፡
የሆነ ፡ የአኪያ ፡ ልጅ ፡ ባኦስ ፡ ተማማለበት ፤
ናዳብና ፡ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ገባቶንን ፡ ከብ
በው ፡ ነበርና ፡ ባኦስ ፡ በፍልስጥኤም ፡ አገር ፡
፳፰ ባለው ፡ በገባቶን ፡ ገደለው ። በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡
በአሳ ፡ በሦስተኛው ፡ ዓመት ፡ ባኦስ ፡ ናዳብን ፡
፳፱ ፴ ገደለው ፥ በፋንታውም ፡ ነገሠ ። ንጉሥም ፡
በሆነ ፡ ጊዜ ፡ የኢዮርብዓምን ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡
መታ ፤ ኢዮርብዓምም ፡ ስለ ፡ ሠራው ፡ ኃጢ
አት ፥ እስራኤልንም ፡ ስላሳተበት ፥ የእስራኤ
ልንም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ስላስቈጣ
በት ፡ ማስቈጫ ፥ በባሪያው ፡ በሴሎናዊው ፡ በአ
ኪያ ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ እንደ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ቃል ፥ እስኪያጠፋው ፡ ድረስ ፡ ከኢዮ
ርብዓም ፡ አንድ ፡ ትንፋሽ ፡ ያለው ፡ አላስቀረም ።

፴፩ (፴፪) የቀረውም ፡ የናዳብ ፡ ነገርና ፡ ያደረገው ፡
ሁሉ ፥ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽ
ሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ?

፴፫ በይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ በአሳ ፡ በሦስተኛው ፡
ዓመት ፡ የአኪያ ፡ ልጅ ፡ ባኦስ ፡ በእስራኤል ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ በቴርሳ ፡ ንጉሥ ፡ ሆኖ ፡ ሀያ ፡ አራት ፡
፴፬ ዓመት ፡ ነገሠ ። በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡
አደረገ ፥ በኢዮርብዓምም ፡ መንገድ ፡ እስራኤ
ልንም ፡ ባሳተበት ፡ ኃጢአት ፡ ሄደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ፡፡

፩ ፡ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ በባኦስ ፡ ላይ ፡ እን
ዲህ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ አናኒ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢዩ ፡
፪ ፡ መጣ ፡፡ እኔ ፡ ከመሬት ፡ አስነሥቼ ፡ በሕዝቤ ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ አድርጌሃለሁ ፤ አንተ ፡
ግን ፡ በኢዮርብዓም ፡ መንገድ ፡ ሄደሃል ፥ በኃ
ጢአታቸውም ፡ ያስቈጡኝ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝቤን ፡
፫ ፡ እስራኤልን ፡ አስተሃቸዋል ፡፡ ስለዚህም ፥ እነሆ ፥
በኦስንና ፡ ቤቱን ፡ ፈጽሜ ፡ እጠርጋለሁ ፤ ቤት
ህንም ፡ እንደ ፡ ናባጥ ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ኢዮርብዓም ፡
፬ ፡ ቤት ፡ አደርጋለሁ ፡፡ ከባኦስም ፡ ወገን ፡ በከተ
ማይቱ ፡ ውስጥ ፡ የሚሞተውን ፡ ውሾች ፡ ይበ
ሉታል ፤ በሜዳውም ፡ የሚሞተውን ፡ የሰማይ ፡
ወፎች ፡ ይበሉታል ፡፡
፭ ፡ የቀረውም ፡ የባኦስ ፡ ነገር ፥ ሥራውና ፡ ጭከ
ናውም ፥ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽ
፮ ፡ ሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ባኦስም ፡ ከአባ
ቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በቴርሳም ፡ ተቀበረ ፤
፯ ፡ ልጁም ፡ ኤላ ፡ በፋንታው ፡ ነገሠ ፡፡ በእጁም ፡
ሥራ ፡ ያስቈጣው ፡ ዘንድ ፥ እንደ ፡ ኢዮርብ
ዓም ፡ ቤት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ስላደረ
ገው ፡ ክፋት ፡ ሁሉ ፡ እርሱንም ፡ ስለ ፡ ገደለው ፥
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በባኦስና ፡ በቤቱ ፡ ላይ ፡
ወደ ፡ አናኒ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡ ወደ ፡ ኢዩ ፡
መጣ ፡፡
፰ ፡ በይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ በአሳ ፡ በሀያ ፡ ስድስተ
ኛው ፡ ዓመት ፡ የባኦስ ፡ ልጅ ፡ ኤላ ፡ በእስራ
ኤል ፡ ላይ ፡ በቴርሳ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፡፡
፱ ፡ የእኩሌቶቹም ፡ ሰረገሎች ፡ አለቃ ፡ ዘምሪ ፡ ተማ
ማለበት ፤ ኤላም ፡ በቴርሳ ፡ ነበረ ፥ በቴርሳም ፡
በነበረው ፡ በቤት ፡ አሽከሮች ፡ አለቃ ፡ በአሳ ፡
፲ ፡ ቤት ፡ ይሰክር ፡ ነበር ፡፡ በይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡
በአሳ ፡ በሀያ ፡ ሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ ዘምሪ ፡
ገብቶ ፡ መታው ፡ ገደለውም ፥ በፋንታውም ፡
፲፩ ፡ ነገሠ ፡፡ ንጉሥም ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፥ በዙፋኑም ፡
በተቀመጠ ፡ ጊዜ ፥ የባኦስን ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡
መታ ፤ ከዘመዶችና ፡ ከወዳጆች ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡
፲፪ ፡ ፲፫ ፡ ወንድ ፡ እንኳ ፡ አልቀረም ፡፡ ባኦስና ፡ ልጁ ፡
ኤላ ፡ ስለ ፡ ሠሩት ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፥ በምናም
ንቴም ፡ ሥራቸው ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡
እግዚአብሔርን ፡ ያስቈጡት ፡ ዘንድ ፡ እስራኤ
ልን ፡ ስለ ፡ አሳቱበት ፡ ኃጢአት ፥ በነቢዩ ፡
በኢዩ ፡ እጅ ፡ በባኦስ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡
እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ዘምሪ ፡ የባኦስን ፡
፲፬ ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ አጠፋ ፡፡ የቀረውም ፡
የኤላ ፡ ነገር ፥ ያደረገውም ፡ ሁሉ ፥ በእስራኤል ፡
ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይ
ደለምን ?
፲፭ ፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በአሳ ፡ በሀያ ፡ ሰበተኛው ፡
ዓመት ፡ ዘምሪ ፡ በቴርሳ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ነገሠ ፡፡
ሕዝቡም ፡ በፍልስጥኤም ፡ አገር ፡ የነበረው ፡
፲፮ ፡ ገባቶንን ፡ ከብበው ፡ ነበር ፡፡ ከተማይቱንም ፡ ከብ
በው ፡ የነበሩ ፡ ሕዝብ ፡ ዘምሪ ፡ እንደ ፡ ዐመፀ ፥
ንጉሡንም ፡ እንደ ፡ ገደለ ፡ ሰሙ ፤ እስራኤልም ፡
ሁሉ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ በሰፈሩ ፡ ውስጥ ፡ የሠራዊ
፲፯ ፡ ቱን ፡ አለቃ ፡ ዘንበሪን ፡ አነገሡ ፡፡ ዘንበሪም ፡ ከእር
ሱም ፡ ጋር ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ከገባቶን ፡ ወጥ
፲፰ ፡ ተው ፡ ቴርሳን ፡ ከበቡ ፡፡ ዘምሪም ፡ ከተማይቱ ፡
እንደ ፡ ተያዘች ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቤት ፡
ግንብ ፡ ውስጥ ፡ ገባ ፥ የንጉሡንም ፡ ቤት ፡ በራሱ ፡
፲፱ ፡ ላይ ፡ በእሳት ፡ አቃጠለ ፤ ስላደረገውም ፡ ኃጢ
አት ፥ እስራኤልንም ፡ ስላሳተበት ፡ ኃጢአት ፥
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አድርጎአልና ፥
በኢዮርብዓምም ፡ መንገድ ፡ ሄዶአልና ፡ ሞተ ፡፡
፳ ፡ የቀረውም ፡ የዘምሪ ፡ ነገር ፥ ያደረገውም ፡
ዐመፅ ፥ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽ
ሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ?
፳፩ ፡ በዚያም ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ሕዝብ ፡ በሁ
ለት ፡ ተከፈለ ፤ የሕዝቡም ፡ እኩሌታ ፡ የጎናትን ፡
ልጅ ፡ ታምኒን ፡ ያነግሡት ፡ ዘንድ ፡ ተከተለው ፤
፳፪ ፡ እኩሌታውም ፡ ዘንበሪን ፡ ተከተለ ፡፡ ዘንበሪንም ፡
የተከተለ ፡ ሕዝብ ፡ የጎናትን ፡ ልጅ ፡ ታምኒን ፡
በተከተለ ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ በረታ ፤ ታምኒም ፡
፳፫ ፡ ሞተ ፥ ዘንበሪም ፡ ነገሠ ፡፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡
በአሳ ፡ በሠላሳ ፡ አንደኛው ፡ ዓመት ፡ ዘንበሪ ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡
ነገሠ ፡፡ በቴርሳም ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፡፡
፳፬ ፡ ከሳምርም ፡ በሁለት ፡ መክሊት ፡ ብር ፡ የሰማር
ያን ፡ ተራራ ፡ ገዛ ፤ በተራራውም ፡ ላይ ፡ ሠራ ፥
የሠራውንም ፡ ከተማ ፡ በተራራው ፡ ባለቤት ፡
፳፭ ፡ በሳምር ፡ ስም ፡ ሰማርያ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ፡፡ ዘን
በሪም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ፥
ከእርሱም ፡ አስቀድሞ ፡ ከነበሩት ፡ ይልቅ ፡
፳፮ ፡ አጅግ ፡ ከፋ ፡፡ በናባጥም ፡ ልጅ ፡ በኢዮርብ
ዓም ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ በምናምንቴም ፡ ነገራ
ቸው ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ ያስቈጡት ፡ ዘንድ ፡ እስራኤልን ፡ ባሳተ
፳፯ ፡ በት ፡ ኃጢአት ፡ ሄደ ፡፡ የቀረውም ፡ ዘንበሪ ፡
ያደረገው ፡ ነገር ፥ የሠራውም ፡ ጭከና ፥ በእስ
ራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተ
፳፰ ፡ ጻፈ ፡ አይደለምን ? ዘንበሪም ፡ ከአባቶቹ ፡
ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በሰማርያም ፡ ተቀበረ ፤ ልጁም ፡
አክዓብ ፡ በፋንታው ፡ ነገሠ ፡፡
፳፱ ፡ በይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ በአሳ ፡ በሠላሳ ፡ ስምን
ተኛው ፡ ዓመት ፡ የዘንበሪ ፡ ልጅ ፡ አክዓብ ፡ በእ
ስራኤል ፡ ላይ ፡ ነገሠ ፤ የዘንበሪም ፡ ልጅ ፡ አክ
ዓብ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ በሰማርያ ፡ ሀያ ፡ ሁለት ፡
፴ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፡፡ የዘንበሪም ፡ ልጅ ፡ አክዓብ ፡
ከእርሱ ፡ በፊት ፡ ከነበሩት ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡
፴፩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ፡፡ በናባ
ጥም ፡ ልጅ ፡ በኢዮርብዓም ፡ ኃጢአት ፡ መሄድ ፡
ታናሽ ፡ ነገር ፡ መሰለው ፥ የሲዶናውያንንም ፡
ንጉሥ ፡ የኤትበአልን ፡ ልጅ ፡ ኤልዛቤልን ፡
አገባ ፥ ሄዶም ፡ በአልን ፡ አመለከ ፡ ሰገደለትም ፡፡
፴፪ ፡ በሰማርያም ፡ በሠራው ፡ በበአል ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡
፴፫ ፡ ለበአል ፡ መሠዊያ ፡ አቆመ ፡፡ አክዓብም ፡ የማ
ምለኪያ ፡ ዐፀድ ፡ ተከለ ፤ አክዓብም ፡ ከእርሱ ፡

በፊት ፡ ከነበሩት ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ፡ የእስራኤልን፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚያስቈጣውን፡ ፴፬፤ ነገር ፡ አበዛ ። በእርሱም ፡ ዘመን ፡ የቤቴል ፡ ሰው ፡ አኪኤል ፡ ኢያሪኮን ፡ ሠራ ፤ በነዌም ፡ ልጅ፡ በኢያሱ ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ተነገረው ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ÷ በበኵር ፡ ልጁ ፡ በአቢሮን ፡ መሠረትዋን ፡ አደረገ ÷ በታናሹ ፡ ልጁም ፡ በሠጉብ ፡ በሮችዋን ፡ አቆመ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩፤ በገለዓድ ፡ ቴስቢ ፡ የነበረው ፡ ቴስብያዊው ፡ ኤልያስ ፡ አክዓብን ፡— በፊቱ ፡ የቆምሁት ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን! ከአፌ ፡ ቃል ፡ በቀር ፡ በእነዚህ ፡ ዓመታት ፡ ፪፤ ጠልና ፡ ዝናብ ፡ አይሆንም ፡ አለው ። የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ለእርሱ ፡ ፫፤ መጣለት ፡— ከዚህ ፡ ተነሥተህ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ሂድ ÷ በዮርዳኖስም ፡ ትይዩ ፡ ባለው ፡ ፬፤ በኮራት ፡ ፈፋ ፡ ውስጥ ፡ ተሸሸግ ። ከወንዙም ፡ ትጠጣለህ ÷ ቍራዎችም ፡ በዚያ ፡ ይመግቡህ ፡ ፭፤ ዘንድ ፡ አዝዣለሁ ። ሄደም ÷ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃልም ፡ አደረገ ። ሄዶም ፡ በዮርዳኖስ ፡ ትይዩ ፡ ባለው ፡ በኮራት ፡ ፈፋ ፡ ውስጥ ፡ ተቀ ፮፤ መጠ ። ቍራዎቹም ፡ በየጥዋትና ፡ በየማታው ፡ እንጀራና ፡ ሥጋ ፡ ያመጡለት ፡ ነበር ፤ ከወን ፯፤ ዙም ፡ ይጠጣ ፡ ነበር ። ከብዙ ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ዝናብ ፡ አልነበረምና ፡ ወንዙ ፡ ደረቀ ።

፰፤፱፤ ተነሥተህም ፡ በሲዶና ፡ አጠገብ ፡ ወዳለችው ፡ ወደ ፡ ሰራፕታ ፡ ሂድ ÷ በዚያም ፡ ተቀመጥ ፤ እነሆም ÷ ትመግብህ ፡ ዘንድ ፡ አንዲት ፡ ባልቴት ፡ አዝዣለሁ ፡ የሚል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፲፤ ቃል ፡ መጣለት ። ተነሥቶም ፡ ወደ ፡ ሰራፕታ ፡ ሄደ ፤ ወደ ፡ ከተማይቱም ፡ በር ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ አንዲት ፡ ባልቴት ፡ በዚያ ፡ እንጨት ፡ ትለቅም ፡ ነበር ፤ እርሱም ፡ ጠርቶ ፡— የምጠጣው ፡ ጥቂት ፡ ውኃ ፡ በጽዋ ፡ ታመጭልኝ ፡ ዘንድ ፡ እለምንሻ ፲፩፤ ለሁ ፡ አላት ። ውኃም ፡ ልታመጣለት ፡ በሄደች ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ጠርቶ ፡— ቍራሽ ፡ እንጀራ ፡ በእጅሽ ፡ ይዘሽ ፡ ትመጭ ፡ ዘንድ ፡ እለ ፲፪፤ ምንሻለሁ ፡ አላት ። እርስዋም ፡— አምላክህ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን! በማድጋ ፡ ካለው ፡ ከእፍኝ ፡ ዱቄት ÷ በማሰሮም ፡ ካለው ፡ ከጥቂት ፡ ዘይት ፡ በቀር ፡ እንጀራ ፡ የለኝም ፤ እነሆም ÷ ገብቼ ፡ ለእኔና ፡ ለልጄ ፡ እጋግረው ፡ ዘንድ ፡ በልተነውም ፡ እንሞት ፡ ዘንድ ፡ ጥቂት ፡ እንጨት ፡ እሰ ፲፫፤ በስባለሁ ፡ አለች ። ኤልያስም ፡ አላት ፡— አትፍሪ ፤ ይልቅስ ፡ ሄደሽ ፡ እንዳልሺው ፡ አድርጊ ፤ አስቀድመሽ ፡ ግን ፡ ከዱቄቱ ፡ ለእኔ ፡ ታናሽ ፡ እንጎቻ ፡ አድርገሽ ፡ አምጭልኝ ÷ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ፲፬፤ ለአንቺና ፡ ለልጅሽ ፡ አድርጊ ፤ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— በምድር ፡ ላይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዝናብ ፡ እስኪሰጥበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ÷ ዱቄቱ ፡ ከማድጋ ፡ አይጨረስም ÷ ዘይቱም ፡ ከማሰሮው ፡ አይጎ ፲፭፤ ድልም ። እርስዋም ፡ ሄዳ ፡ እንደ ፡ ኤልያስ ፡ ቃል ፡ አደረገች ፤ እርስዋና ፡ እርሱ ፡ ቤትዋም ፡ ፲፮፤ ብዙ ፡ ቀን ፡ በሉ ። በኤልያስም ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ዱቄቱ ፡ ከማድጋው ፡ አልተጨረሰም ÷ ዘይቱም ፡ ከማሰሮው ፡ አልጐደለም ።

፲፯፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የባለቤቲቱ ፡ ልጅ ፡ ታመመ ፤ ትንፋሹም ፡ እስኪታጣ ፡ ድረስ ፡ ደዌው ፡ እጅግ ፡ ፲፰፤ ከበድ ፡ ነበረ ። እርስዋም ፡ ኤልያስን ፡— የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ሆይ ÷ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አለኝ ? ኃጢአቴንስ ፡ ታሳስብ ፡ ዘንድ ÷ ልጄንስ ፡ ትገድል ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጥተሃ ፲፱፤ ልን ? አለችው ። ኤልያስም ፡— ልጅሽን ፡ ስጪኝ ፡ አላት ። ከብብትዋም ፡ ወስዶ ፡ ተቀምጦበት ፡ ወደ ፡ ነበረው ፡ ሰገነት ፡ አወጣው ፡ ፳፤ በአልጋውም ፡ ላይ ፡ አጋደመው ። ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡— አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ÷ ልጅዋን ፡ በመግደልህ ፡ ይህችን ፡ ትቀልበኝ ፡ የነበረችቱን ፡ ባልቴት ፡ እንዲህ ፡ ደግሞ ፡ አስጨነ ፳፩፤ ቅኻትን ? ብሎ ፡ ጮኸ ። በብላቴናውም ፡ ላይ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ተዘረጋበት ÷ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡— አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ÷ የዚህ ፡ ብላቴና ፡ ነፍስ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ትመለስ ፡ ዘንድ ፡ ፳፪፤ እለምንሃለሁ ፡ ብሎ ፡ ጮኸ ። እግዚአብሔርም ፡ የኤልያስን ፡ ቃል ፡ ሰማ ፤ የብላቴናው ፡ ነፍስ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተመለሰች ÷ እርሱም ፡ ዳነ ። ፳፫፤ ኤልያስም ፡ ብላቴናውን ፡ ይዞ ፡ ከሰገነቱ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ አወረደው ÷ ኤልያስም ፡— እነሆ ÷ ልጅሽ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራል ፡ ብሎ ፡ ለእናቱ ፡ ሰጣት ። ፳፬፤ ሴቲቱም ፡ ኤልያስን ፡— የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሆንህ ÷ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ በአፍህ ፡ እውነት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አሁን ፡ አወቅሁ ፡ አለችው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩፤ ከብዙ ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ በሦስተኛው ፡ ዓመት ፡— ሂድ ÷ ለአክዓብ ፡ ተገለጥ ÷ በምድር ፡ ላይም ፡ ዝናብ ፡ እሰጣለሁ ፡ የሚል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ኤልያስ ፡ መጣ ። ፪፤ ኤልያስም ፡ ለአክዓብ ፡ ይገለጥ ፡ ዘንድ ፡ ሄደ ፤ በሰማርያም ፡ ራብ ፡ ጸንቶ ፡ ነበር ። ፫፤ አክዓብም ፡ የቤቱን ፡ አዛዥ ፡ አብድዩን ፡ ጠራ ፤ አብድዩ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እጅግ ፡ ይፈራ ፡ ነበር ። ፬፤ ኤልዛቤልም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ነቢያት ፡ ባስገደለች ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ መቶውን ፡ ነቢያት ፡ ወስዶ ፡ አምሳ ፡ አምሳውን ፡ በዋሻ ፡ ውስጥ ፡ ሸሽጎ ፡ እንጀራና ፡ ውኃ ፡ ይመግባቸው ፡ ነበር ። ፭፤ አክዓብም ፡ አብድዩን ፡— በአገሩ ፡ መካከል ፡ ወደ ፡ ውኃው ፡ ምንጭ ፡ ሁሉና ፡ ወደ ፡ ወንዝ ፡ ሁሉ ፡ ሂድ ፤ እንስሶችም ፡ ሁሉ ፡ እንዳይጠፉ ፡ ፈረሶችንና ፡ በቅሎችን ፡ የምናድንበት ፡ ሣር ፡ ምናልባት ፡ እናገኛለን ፡ አለው ። ፮፤ ሁለቱም ፡ የሚመለሱበትን ፡ አገር ፡ ተካፈሉ ፤ አክዓብም ፡ ለብቻው ፡

በአንድ፡መንገድ፥አብድዩም፡ለብቻው፡በሌላ፡
መንገድ፡ሄዱ ።

፯፤ አብድዩም፡በመንገድ፡ሲሄድ፥እነሆ፥ኤል
ያስ፡ ተገናኘው ፤ አብድዩም ፡ አወቀው ፥ በግ
ምባሩም ፡ ተደፍቶ ፡— ጌታዬ፡ሆይ፥ኤልያስ፡
፰፤ አንተ፡ነህን ? አለ ። ኤልያስም ፡— እኔ ፡ ነኝ ፤
ሄደህ ፡ ለጌታህ ፡— ኤልያስ፡ተገኝቶአል፡በል ፡
፱፤ አለው ። አብድዩም ፡ አለ ፡— እኔን፡ባሪያህን፡እን
ዲገድል ፡ በአክዓብ፡እጅ፡አሳልፈህ ፡ ትሰጠኝ፡
፲፤ ዘንድ ፡ ምን ፡ ኃጢአት ፡ አድርጌአለሁ ? አም
ላክህ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! ጌታዬ ፡ ይፈ
ልግህ ፡ ዘንድ ፡ ያልላከበት ፡ ሕዝብ ፡ ወይም ፡
መንግሥት ፡ የለም ፤ ሁሉም ፡— በዚህ ፡ የለም፡
ባሉ ፡ ጊዜ ፡ አንተን ፡ እንዳላገኙ ፡ መንግሥቱ
፲፩፤ ንና ፡ ሕዝቡን ፡ አምሎአቸው ፡ ነበር ። አሁ
ንም ፥ እነሆ ፡— ሂድ ፥ ኤልያስ ፡ ተገኘ ፡ ብለህ፡
፲፪፤ ለጌታህ ፡ ንገር ፡ ትለኛለህ ። እኔም ፡ ከአንተ ፡
ጥቂት ፡ ራቅ ፡ ስል ፡ የእግዚአብሔር፡መንፈስ፡
አንሥቶ ፡ ወደማላውቀው ፡ ስፍራ ፡ ይወስድ
ሃል ፤ እኔም ፡ ገብቼ ፡ ለአክዓብ ፡ ስናገር ፥ ባያ
ገኝህ ፡ ይገድለኛል ፤ እኔም ፡ ባሪያህ ፡ ከትንሽ
ነቴ ፡ ጀምሬ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እፈራ ፡ ነበር ።
፲፫፤ ኤልዛቤል ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ነቢያት ፡ ባስገ
ደለች ፡ ጊዜ ፥ መቶውን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነቢ
ያት ፡ ወስጄ ፥ አምሳ ፡ አምሳውንም ፡ በዋሻ ፡
ውስጥ ፡ ሸሽጌ ፥ እንጀራና ፡ ውኃ ፡ የመገብኋ
ቸው ፥ ይህ ፡ ያደረግሁት ፡ ነገር ፡ በውኑ ፡ ለጌ
፲፬፤ ታዬ ፡ አልታወቀህምን ? አሁንም ፡— ሄደህ ፡
ኤልያስ ፡ ተገኘ ፡ ብለህ ፡ ለጌታህ ፡ ንገር ፡ ትላ
፲፭፤ ለህ ፤ እርሱም ፡ ይገድለኛል ። ኤልያስም ፡—
በፊቱ ፡ የቆምሁት ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ሕያው ፡
እግዚአብሔርን ! እኔ ፡ ዛሬ ፡ ለእርሱ ፡ እገለጣ
ለሁ ፡ አለ ።

፲፮፤ አብድዩም ፡ አክዓብን ፡ ሊገናኘው ፡ ሄደ ፥ ነገ
ረውም ፤ አክዓብም ፡ ኤልያስን ፡ ሊገናኘው ፡
፲፯፤ መጣ ። አክዓብም ፡ ኤልያስን ፡ ባየው ፡ ጊዜ ፡—
እስራኤልን ፡ የምትገለባብጥ ፡ አንተ ፡ ነህን ?
፲፰፤ አለው ። ኤልያስም ፡— እስራኤልን ፡ የምትገ
ለባብጡ ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ትታ
ችሁ ፡ በአሊምን ፡ የተከተላችሁ ፥ አንተና ፡ የአ
ባትህ ፡ ቤት ፡ ናችሁ ፡ እንጂ ፡ እኔ ፡ አይደለሁም ።
፲፱፤ አሁንም ፡ ልከህ ፡ እስራኤልን ፡ ሁሉ ፥ በኤልዛ
ቤልም ፡ ማዕድ ፡ የሚበሉትን ፡ አራት ፡ መቶ ፡
አምሳ ፡ የበኣልን ፡ ነቢያት ፥ አራት ፡ መቶም ፡
የማምለኪያ ፡ ዐፀድን ፡ ነቢያት ፡ ወደ ፡ እኔ ፡
ወደ ፡ ቀርሜሎስ ፡ ተራራ ፡ ሰብስብ ፡ አለ ።

፳፤ አክዓብም ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡
ልከ ፡ ነቢያቱን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ቀርሜሎስ ፡ ተራራ ፡
፳፩፤ ሰበሰበ ። ኤልያስም ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡
ቀርቦ ፡— እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ በሁለት ፡ አሳብ ፡
ታነክሳላችሁ ? እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ቢሆን ፡
እርሱን ፡ ተከተሉ ፤ በኣል ፡ ግን ፡ አምላክ ፡
ቢሆን ፡ እርሱን ፡ ተከተሉ ፡ አለ ። ሕዝቡም ፡
፳፪፤ አንዲት ፡ ቃል ፡ አልመለሱለትም ። ኤልያስም ፡
ሕዝቡን ፡ አለ ፡— ከእግዚአብሔር ፡ ነቢያት ፡
እኔ ፡ ብቻ ፡ ቀርቻለሁ ፤ የበኣል ፡ ነቢያት ፡ ግን ፡
፳፫፤ አራት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ሰዎች ፡ ናቸው ። ሁለት ፡
ወይፈኖች ፡ ይሰጡን ፤ እነርሱም ፡ አንድ ፡ ወይ
ፈን ፡ ይምረጡ ፥ እየብልቱም ፡ ይቍረጡት ፥
በእንጨትም ፡ ላይ ፡ ያኑሩት ፥ በበታቹም ፡
እሳት ፡ አይጨምሩ ፤ እኔም ፡ ሁለተኛውን ፡ ወይ
ፈን ፡ አዘጋጃለሁ ፥ በእንጨቱም ፡ ላይ ፡ አኖረ
ዋለሁ ፥ በበታቹም ፡ እሳት ፡ አልጨምርም ።
፳፬፤ እናንተም ፡ የአምላካችሁን ፡ ስም ፡ ጥሩ ፥ እኔም ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ እጠራለሁ ፤ ሰምቶም ፡
በእሳት ፡ የሚመልስ ፡ አምላክ ፥ እርሱ ፡ አም
ላክ ፡ ይሁን ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡— ይህ ፡ ነገር ፡
መልካም ፡ ነው ፡ ብለው ፡ መለሱ ።

፳፭፤ ኤልያስም ፡ የበኣልን ፡ ነቢያት ፡— እናንተ ፡
ብዙዎች ፡ ናችሁና ፡ አስቀድማችሁ ፡ አንድ ፡
ወይፈን ፡ ምረጡና ፡ አዘጋጁ ፤ የአምላካችሁ
ንም ፡ ስም ፡ ጥሩ ፥ በበታቹም ፡ እሳት ፡ አትጨ
፳፮፤ ምሩ ፡ አላቸው ። ወይፈኑንም ፡ ወስደው ፡ አዘ
ጋጁ ፥ ከጥዋትም ፡ እስከ ፡ ቀትር ፡ ድረስ ፡—
በኣል ፡ ሆይ ፥ ስማን ፡ እያሉ ፡ የበኣልን ፡ ስም ፡
ጠሩ ። ድምፅም ፡ አልነበረም ፥ የሚመልስም ፡
አልነበረም ፤ በሠሩትም ፡ መሠዊያ ፡ ዙሪያ ፡ እያ
፳፯፤ ነከሱ ፡ ያሸበሽቡ ፡ ነበር ። በቀትርም ፡ ጊዜ ፡
ኤልያስ ፡— አምላክ ፡ ነውና ፡ በታላቅ ፡ ቃል ፡
ጩኹ ፤ ምናልባት ፡ አሳብ ፡ ይዞታል ፥ ወይም ፡
ፈቀቅ ፡ ብሎአል ፥ ወይም ፡ ወደ ፡ መንገድ ፡ ሄዶ
አል ፥ ወይም ፡ ተኝቶ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ መቀስቀስ ፡
፳፰፤ ያስፈልገዋል ፡ እያለ ፡ አላገጠባቸው ። በታላ
ቅም ፡ ቃል ፡ ይጮኹ ፥ እንደ ፡ ልማዳቸውም ፡
ደማቸው ፡ እስኪፈስስ ፡ ድረስ ፡ ገላቸውን ፡ በካ
፳፱፤ ራና ፡ በቀጭኔ ፡ ይብዋጭሩ ፡ ነበር ። ቀትርም ፡
ካለፈ ፡ በኋላ ፡ መሥዋዕተ ፡ ሠርክ ፡ እስኪደ
ርስ ፡ ትንቢት ፡ ይናገሩ ፡ ነበር ፤ ድምፅም ፡ አል
ነበረም ፥ የሚመልስና ፡ የሚያደምጥም ፡ አልነ
በረም ።

፴፤ ኤልያስም ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡— ወደ ፡ እኔ ፡
ቅረቡ ፡ አላቸው ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡
ቀረቡ ። ፈርሶ ፡ የነበረውንም ፡ የእግዚአብሔ
፴፩፤ ርን ፡ መሠዊያ ፡ አበጀ ። ኤልያስም ፡— ስምህ ፡
እስራኤል ፡ ይሆናል ፡ የሚል ፡ የእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ እንደ ፡ ደረሰለት ፡ እንደ ፡ ያዕቆብ ፡ ልጆች ፡
ነገድ ፡ ቍጥር ፡ አሥራ ፡ ሁለቱን ፡ ድንጋዮች ፡
፴፪፤ ወሰደ ። ከድንጋዮችም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስም ፡
መሠዊያ ፡ ሠራ ፤ በመሠዊያውም ፡ ዙሪያ ፡
ሁለት ፡ መስፈሪያ ፡ እህል ፡ የሚይዝ ፡ ጕድ
፴፫፤ ጓድ ፡ ቈፈረ ። እንጨቱንም ፡ በተርታ ፡ አደ
ረገ ፥ ወይፈኑንም ፡ በብልት ፡ በብልቱ ፡ ቈረጠ ፥
፴፬፤ በእንጨቱም ፡ ላይ ፡ አኖረና ፡— አራት ፡ ጋን ፡
ውኃ ፡ ሙሉ ፡ በሚቃጠለው ፡ መሥዋዕትና ፡
በእንጨቱ ፡ ላይ ፡ አፍስሱ ፡ አለ ። ደግሞም ፡—
ድገሙ ፡ አለ ፤ እነርሱም ፡ ደገሙ ። እርሱም ፡—
ሦስተኛ ፡ አድርጉ ፡ አለ ፤ ሦስትኛም ፡ አደረጉ ።
፴፭፤ ውኃውም ፡ በመሠዊያው ፡ ዙሪያ ፡ ፈሰሰ ፤ ደግ

፴፮ ሞም ፡ ጕድጓዱን ፡ በውኃ ፡ ሞላው ። መሥዋዕተ ፡ ሠርክ ፡ በሚቀርብበት ፡ ጊዜ ፡ ነቢዩ ፡ ኤልያስ ፡ ቀርቦ ፡— አቤቱ ÷ የአብርሃምና ፡ የይስሐቅ ፡ የእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ አንተ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ÷ እኔም ፡ ባሪያህ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ÷ ይህንም ፡ ሁሉ ፡ ፴፯ በቃልህ ፡ እንዳደረግሁ ፡ ዛሬ ፡ ይገለጥ ። አንተ ÷ አቤቱ ÷ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ÷ ልባቸውንም ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ መለስህ ፡ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፡ ስማኝ ÷ አቤቱ ÷ ስማኝ ፡ አለ ። ፴፰ የእግዚአብሔርም ፡ እሳት ፡ ወደቀች ÷ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕቱንም ፡ እንጨቱንም ፡ ድንጋዮቹንም ፡ አፈሩንም ፡ በላች ÷ በጕድጓዱም ፡ ፴፱ ውስጥ ፡ ያለውን ፡ ውኃ ፡ ላሰች ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ያንን ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ በግምባራቸው ፡ ተደፍተው ፡— እግዚአብሔር ፡ እርሱ ፡ አምላክ ፡ ነው ÷ እግዚአብሔር ፡ እርሱ ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ ፵ አሉ ። ኤልያስም ፡— ከበኣል ፡ ነቢያት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ እንዳያመልጥ ፡ ያዙ ፡ አላቸው ። ያዙአቸውም ፤ ኤልያስም ፡ ወደ ፡ ቂሶን ፡ ወንዝ ፡ ወስዶ ፡ በዚያ ፡ አሳረዳቸው ።

፵፩ ኤልያስም ፡ አክዓብን ፡— የዝናቡ ፡ ውሽንፍር ፡ እጅግ ፡ ነውና ፡ ተነሥተህ ፡ ውጣ ÷ ብላም ÷ ፵፪ ጠጣም ፡ አለው ። አክዓብም ፡ ሊበላና ፡ ሊጠጣ ፡ ወጣ ፤ ኤልያስም ፡ ወደ ፡ ቀርሜሎስ ፡ አናት ፡ ወጣ ፤ ፊቱንም ፡ በጕልበቱ ፡ መካከል ፡ አድ ፵፫ ርጎ ፡ በግምባሩ ፡ ተደፋ ። ብላቴናውንም ፡— ወጥተህ ፡ ወደ ፡ ባሕሩ ፡ ተመልከት ፡ አለው ። ወጥቶም ፡ ተመልክቶም ፡— ምንም ፡ የለም ፡ አለ ። እርሱም ፡— ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ተመላለስ ፡ አለው ። ብላቴናውም ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ተመላ ፵፬ ለሰ ። በሰባተኛውም ፡ ጊዜ ፡— እነሆ ÷ የሰው ፡ እጅ ፡ የምታህል ፡ ታናሽ ፡ ደመና ፡ ከባሕር ፡ ወጣች ፡ አለ ። እርሱም ፡— ወጥተህ ፡ አክዓብን ፡— ዝናብ ፡ እንዳይከለክልህ ፡ ሰረገላን ፡ ፵፭ ጭነህ ፡ ውረድ ፡ በለው ፡ አለ ። ከጥቂትም ፡ ጊዜ ፡ በኋላ ፡ ሰማዩ ፡ ከደመናውና ፡ ከነፋሱ ፡ የተነሣ ፡ ጨለመ ÷ ብዙም ፡ ዝናብ ፡ ሆነ ፤ አክዓብም ፡ በሰረገላው ፡ ተቀምጦ ፡ ወደ ፡ ኢይዝራ ፵፮ ኤል ፡ ሄደ ። የእግዚአብሔርም ፡ እጅ ፡ በኤልያስ ፡ ላይ ፡ ነበረች ፤ ወገቡንም ፡ አሸንፍጦ ፡ ወደ ፡ ኢይዝራኤል ፡ እስኪገባ ፡ ድረስ ፡ በአክዓብ ፡ ፊት ፡ ይሮጥ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ አክዓብም ፡ ኤልያስ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ እንዳደረገ ÷ ነቢያትንም ፡ ሁሉ ፡ በሰይፍ ፡ እንደ ፡ ፪ ገደለ ፡ ለኤልዛቤል ፡ ነገራት ። ኤልዛቤልም ፡— ነገ ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ነፍስህን ፡ ከእነዚህ ፡ እንደ ፡ አንዲቱ ፡ ነፍስ ፡ ባላደርጋት ÷ አማልክት ፡ ይህን ፡ ያድርጉብኝ ፡ ይህንም ፡ ይጨምሩብኝ ፡ ብላ ፡ ወደ ፡ ኤልያስ ፡ መልእክተኛ ፡ ላከች ። ፫ ኤልያስም ፡ ፈርቶ ፡ ተነሣ ÷ ነፍሱንም ፡ ሊያድን ፡ ሄደ ÷ በይሁዳም ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ ቤርሳቤህ ፡ መጥቶ ፡ ብላቴናውን ፡ በዚያ ፡ ተወ ። ፬ እርሱም ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ የሚያህል ፡ መንገድ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ሄደ ፤ መጥቶም ፡ ከክትክታ ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ ተቀመጠና ፡— ይበቃኛል ፤ አሁንም ÷ አቤቱ ÷ እኔ ፡ ከአባቶቼ ፡ አልበልጥምና ፡ ነፍሴን ፡ ውሰድ ፡ ብሎ ፡ እንዲሞት ፡ ለመነ ። ፭ በክትክታውም ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ ተጋደመ ፡ እንቅልፍም ፡ አንቀላፋ ፤ እነሆም ÷ መልአክ ፡ ዳሰሰውና ፡— ተነሥተህ ፡ ብላ ፡ አለው ። ፮ ሲመለከትም ÷ እነሆ ÷ በራሱ ፡ አጠገብ ፡ የተጋገረ ፡ እንጐቻና ፡ በማሰሮ ፡ ውኃ ፡ አገኘ ። በላም ፡ ጠጣም ÷ ተመልሶም ፡ ተኛ ። ፯ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ ደግሞ ፡ ሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡ መጥቶ ፡ ዳሰሰውና ፡— የምትሄድበት ፡ መንገድ ፡ሩቅ ፡ ነውና ፡ ተነሥተህ ፡ ብላ ፡ አለው ። ፰ ተነሥቶም ፡ በላ ፡ ጠጣም ፤ በዚያም ፡ ምግብ ፡ ኃይል ፡ እስከ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተራራ ፡ እስከ ፡ ኮሬብ ፡ ድረስ ፡ አርባ ፡ ቀንና ፡ አርባ ፡ ሌሊት ፡ ሄደ ።

፱ እዚያም ፡ ወዳለ ፡ ዋሻ ፡ መጣ ÷ በዚያም ፡ አደረ ፤ እነሆም ፡— ኤልያስ ሆይ ÷ በዚህ ፡ ምን ፡ ታደርጋለህ ? የሚል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጣ ። ፲ እርሱም ፡— ለሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እጅግ ፡ ቀንቻለሁ ፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ቃል ፡ ኪዳንህን ፡ ትተዋልና ÷ መሠዊያዎችህንም ፡ አፍርሰዋልና ÷ ነቢያትህንም ፡ በሰይፍ ፡ ገድለዋልና ፤ እኔም ፡ ብቻዬን ፡ ቀርቻለሁ ፤ ነፍሴንም ፡ ሊወስዱአት ፡ ይሻሉ ፡ አለ ። ፲፩ እርሱም ፡— ውጣ ÷ በተራራውም ፡ ላይ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቁም ፡ አለ ። እነሆም ÷ እግዚአብሔር ፡ አለፈ ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ትልቅና ፡ ብርቱ ፡ ነፋስ ፡ ተራሮቹን ፡ ሰነጠቀ ፡ ዓለቶቹንም ፡ ሰባበረ ÷ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በነፋሱ ፡ ውስጥ ፡ አልነበረም ። ከነፋሱም ፡ በኋላ ፡ የምድር ፡ መናወጥ ፡ ሆነ ÷ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በምድር ፡ ፲፪ መናወጥ ፡ ውስጥ ፡ አልነበረም ። ከምድር ፡ መናወጥ ፡ በኋላ ፡ እሳት ፡ ሆነ ÷ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በእሳቱ ፡ ውስጥ ፡ አልነበረም ። ከእሳቱም ፡ በኋላ ፡ ትንሽ ፡ የዝምታ ፡ ድምፅ ፡ ፲፫ ሆነ ። ኤልያስም ፡ ያን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ፊቱን ፡ በመጐናጸፊያው ፡ ሸፈነ ÷ ወጥቶም ፡ በዋሻው ፡ ደጃፍ ፡ ቆመ ። እነሆ ፡— ኤልያስ ፡ ሆይ ÷ በዚህ ፡ ምን ፡ ታደርጋለህ ? የሚል ፡ ድምፅ ፡ ወደ ፡ ፲፬ እርሱ ፡ መጣ ። እርሱም ፡— ለሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እጅግ ፡ ቀንቻለሁ ፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ቃል ፡ ኪዳንህን ፡ ትተዋልና ÷ መሠዊያዎችህንም ፡ አፍርሰዋልና ÷ ነቢያትህንም ፡ በሰይፍ ፡ ገድለዋልና ፤ እኔም ፡ ብቻዬን ፡ ቀርቻለሁ ፤ ነፍሴንም ፡ ሊወስዱአት ፡ ይሻሉ ፡ አለ ።

፲፭ እግዚአብሔርም ፡ አለው ፡— ሂድ ÷ በመጣህበትም ፡ መንገድ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ ተመለስ ፤ ከዚያም ፡ በደረስህ ፡ ጊዜ ፡ በሶ

ርያ ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ አዛሄልን ፡
፲፮ ቅባው ፤ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ይሆን ፡
ዘንድ ፡ የናሜሲን ፡ ልጅ ፡ ኢዩን ፡ ቅባው ፤ በፋ
ንታህም ፡ ነቢይ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ የአቤልምሖ
ላን ፡ ሰው ፡ የሣፋጥን ፡ ልጅ ፡ ኤልሳዕን ፡ ቅባው ፡
፲፯ ከአዛሄልም ፡ ሰይፍ ፡ ያመለጠውን ፡ ሁሉ ።
ኢዩ ፡ ይገድለዋል ፤ ከኢዩም ፡ ሰይፍ ፡ ያመለ
፲፰ ጠውን ፡ ሁሉ ፡ ኤልሳዕ ፡ ይገድለዋል ። እኔም ፡
ከእስራኤል ፡ ጕልበታቸውን ፡ ለበኣል ፡ ያላንበ
ረከኩትን ፡ ሁሉ ÷ በአፋቸውም ፡ ያልሳሙትን ፡
ሁሉ ÷ ሰባት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ለእኔ ፡ አስቀራለሁ ።
፲፱ ከዚያም ፡ ሄደ ÷ የሣፋጥንም ፡ ልጅ ፡ ኤልሳ
ዕን ፡ በአሥራ ፡ ሁለት ፡ ጥማድ ፡ በሬዎች ፡ ሲያ
ርስ ÷ እርሱም ፡ ከአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ጋር ፡
ሆኖ ፡ አገኘው ። ኤልያስም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡
፳ አልፎ ፡ መጐናጸፊያውን ፡ ጣለበት ። በሬዎቹ
ንም ፡ ተወ ÷ ከኤልያስም ፡ በኋላ ፡ ሮጦ ፡— አባ
ቴንና ፡ እናቴን ፡ እስማቸው ፡ ዘንድ ÷ እባክህ ÷
ተወኝ ÷ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እከተልሃለሁ ፡ አለው ።
እርሱም ፡— ሂድና ፡ ተመለስ ፤ ምን ፡ አድርጌ
፳፩ ልሃለሁ ? አለው ። ከእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ተመ
ልሶ ፡ ሁለቱን ፡ በሬዎች ፡ ወስዶ ፡ አረዳቸው ÷
ሥጋቸውንም ፡ በበሬዎቹ ፡ ዕቃ ፡ ቀቀለው ÷
ለሕዝቡም ፡ ሰጣቸው ÷ በሉም ፤ እርሱም ፡ ተነ
ሥቶ ፡ ኤልያስን ፡ ተከትሎ ፡ ሄደ ÷ ያገለግለ
ውም ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ ለኢይዝራኤላዊውም ፡ ለናቡቴ ፡ በሰማርያ ፡
ንጉሥ ፡ በአክዓብ ፡ ቤት ፡ አጠገብ ፡ የወይን ፡
፪ ቦታ ፡ ነበረው ። አክዓብም ፡ ናቡቴን ፡— በቤቴ ፡
አቅራቢያ ፡ ነውና ፡ የአትክልት ፡ ቦታ ፡ አደር
ገው ፡ ዘንድ ፡ የወይን ፡ ቦታህን ፡ ስጠኝ ፤ ስለ ፡
እርሱም ፡ ከእርሱ ፡ የተሻለ ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡
እሰጥሃለሁ ፤ ወይም ፡ ብትወድድ ፡ ግምቱን ፡ ገን
፫ ዘብ ፡ እሰጥሃለሁ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ። ናቡቴም ፡
አክዓብን ፡— የአባቶቼን ፡ ርስት ፡ እሰጥህ ፡ ዘንድ ፡
፬ እግዚአብሔር ፡ ያርቅልኝ ፡ አለው ። ኢይዝራ
ኤላዊውም ፡ ናቡቴ ፡— የአባቶቼን ፡ ርስት ፡ አል
ሰጥህም ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ ተናገረው ፡ አክዓብ ፡ ተቆ
ጥቶና ፡ ተናድዶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ገባ ። በአልጋ
ውም ፡ ላይ ፡ ተጋድሞ ፡ ፊቱን ፡ ተሸፋፈነ ÷ እን
ጀራም ፡ አልበላም ።
፭ ሚስቱም ፡ ኤልዛቤል ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጥታ ፡—
ልብህ ፡ የሚያዝን ፡ እንጀራስ ፡ የማትበላ ፡ ስለ ፡
፮ ምንድር ፡ ነው ? አለችው ። እርሱም ፡— ኢይዝ
ራኤላዊውን ፡ ናቡቴን ፡— የወይንህን ፡ ቦታ ፡ በገ
ንዘብ ፡ ስጠኝ ፤ ወይም ፡ ብትወድድ ፡ በፋንታው ፡
ሌላ ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ እሰጥሃለሁ ፡ ብዬ ፡ ተናገ
ርሁት ፤ እርሱ ፡ ግን ፡— የወይን ፡ ቦታዬን ፡ አል
ሰጥህም ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ መለሰልኝ ፡ ነው ፡ አላት ።
፯ ሚስቱም ፡ ኤልዛቤል ፡— አንተ ፡ አሁን ፡ የእስ
ራኤልን ፡ መንግሥት ፡ ትገዛለህን ? ተነሣ ፡ እንጀ
ራም ፡ ብላ ÷ ልብህም ፡ ደስ ፡ ይበላት ፤ የኢይ
ዝራኤላዊውን ፡ የናቡቴን ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ እሰ
፰ ጥሃለሁ ፡ አለችው ። በአክዓብም ፡ ስም ፡ ደብ
ዳቤ ፡ ጻፈች ÷ በማኅተሙም ፡ አተመችው ፤
በከተማው ፡ ወደ ፡ ነበሩትና ፡ ከናቡቴም ፡ ጋር ፡
ወደ ፡ ተቀመጡት ፡ ሽማግሌዎችና ፡ ከበርቴ
፱ ዎች ፡ ደብዳቤውን ፡ ላከች ። በደብዳቤውም ፡—
ስለ ፡ ጾም ፡ አዋጅ ፡ ንገሩ ÷ ናቡቴንም ፡ በሕ
፲ ዝቡ ፡ ፊት ፡ አስቀምጡት ፤ ሁለትም ፡ ምናም
ንቴ ፡ ሰዎች ፡ በፊቱ ፡ አስቀምጡና ፡— እግዚአ
ብሔርንና ፡ ንጉሡን ፡ ሰድበአል ፡ ብለው ፡ ይመ
ስክሩበት ፤ አውጥታችሁም ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡
ውገሩት ፡ ብላ ፡ ጻፈች ።
፲፩ በከተማውም ፡ የተቀመጡት ፡ የከተማው ፡
ሰዎችና ፡ ሽማግሌዎች ፡ ከበርቴዎችም ፡ ኤልዛ
ቤል ፡ እንዳዘዘቻቸውና ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ በተላ
ከው ፡ ደብዳቤ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ እንዲሁ ፡ አደረጉ ።
፲፪ የጾም ፡ አዋጅ ፡ ነገሩ ÷ ናቡቴንም ፡ በሕዝቡ ፡
፲፫ ፊት ፡ አስቀመጡት ። ሁለቱም ፡ ምናምንቴ ፡
ሰዎች ፡ ገብተው ፡ በፊቱ ፡ ተቀመጡ ፤ ምናም
ንቴዎቹ ፡ ሰዎችም ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡— ናቡቴ ፡
እግዚአብሔርንና ፡ ንጉሡን ፡ ሰድበአል ፡ ብለው ፡
በናቡቴ ፡ ላይ ፡ መሰከሩ ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ከከ
ተማ ፡ አውጥተው ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ ወገ
፲፬ ሩት ። ወደ ፡ ኤልዛቤልም ፡— ናቡቴ ፡ ተወ
፲፭ ግሮ ፡ ሞተ ፡ ብለው ፡ ላኩ ። ኤልዛቤልም ፡
ናቡቴ ፡ ተወግሮ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ በሰማች ፡ ጊዜ ፡
ኤልዛቤል ፡ አክዓብን ፡— ናቡቴ ፡ ሞቶአል ፡
እንጂ ፡ በሕይወት ፡ አይደለምና ፡ በገንዘብ ፡
ይሰጥህ ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ ያለውን ፡ የኢይዝራ
ኤላዊውን ፡ የናቡቴን ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ ተነሥ
፲፮ ተህ ፡ ውረስ ፡ አለችው ። አክዓብም ፡ ናቡቴ ፡
እንደ ፡ ሞተ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ይወርሰው ፡ ዘንድ ፡
ወደ ፡ ኢይዝራኤላዊው ፡ ወደ ፡ ናቡቴ ፡ ወይን ፡
ቦታ ፡ ሊወርድ ፡ ተነሣ ።
፲፯ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ቴስብያ
ዊው ፡ ወደ ፡ ኤልያስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡—
፲፰ ተነሥተህ ፡ በሰማርያ ፡ የሚኖረውን ፡ የእስራ
ኤልን ፡ ንጉሥ ፡ አክዓብን ፡ ትገናኝ ፡ ዘንድ ፡
ውረድ ፤ እነሆ ÷ ይወርሰው ፡ ዘንድ ፡ በወረደ
በት ፡ በናቡቴ ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ ውስጥ ፡ አለ ።
፲፱ አንተም ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ገድለህ ፡ ወረስኸውን ? ብለህ ፡ ንገረው ። ደግ
ሞም ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ውሾች ፡ የናቡቴን ፡ ደም ፡ በላሱበት ፡ ስፍራ ፡
የአንተን ፡ ደም ፡ ደግሞ ፡ ውሾች ፡ ይልሱታል ፡
፳ ብለህ ፡ ንገረው ። አክዓብም ፡ ኤልያስን ፡—
ጠላቴ ፡ ሆይ ÷ አገኘኸኝን ? አለው ። እርሱም ፡
እንዲህ ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ፡— አግኝቼሃለሁ ፤
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ለማድረግ ፡ ራስ
፳፩ ህን ፡ ሸጠሃልና ። እነሆ ÷ ክፉ ፡ ነገር ፡ አመጣ
ብሃለሁ ÷ ፈጽሞም ፡ እጠርግሃለሁ ÷ ከአክዓ
ብም ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ የታሰረውንና ፡ የተ
፳፪ ለቀቀውን ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ አጠፋለሁ ፤ በሥራ
ህም ፡ አስቈጥተኸኛልና ÷ እስራኤልንም ፡ አስ

ተሃልና ፡ ቤትህን ፡ እንደ ፡ ናባጥ ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡
ኢዮርብዓም ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ አኪያም ፡ ልጅ ፡
፳፫፤ እንደ ፡ በአስ ፡ ቤት ፡ አደርገዋለሁ ። ደግሞ ፡
እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ኤልዛቤል ፡— በኢይዝ
ራኤል ፡ ቅጥር ፡ አጠገብ ፡ ኤልዛቤልን ፡ ውሾች ፡
፳፬፤ ይበሉአታል ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ። ከአክዓብም ፡
ወገን ፡ በከተማይቱ ፡ ውስጥ ፡ የሞተውን ፡
ውሾች ፡ ይበሉታል ፤ በሜዳውም ፡ የሞተውን ፡
፳፭፤ የሰማይ ፡ ወፎች ፡ ይበሉታል ። በእግዚአብ
ሔር ፡ ፊት ፡ ክፉት ፡ ለመሥራት ፡ ራሱን ፡ እንደ ፡
ሸጠ ፥ ሚስቱም ፡ ኤልዛቤል ፡ እንደ ፡ ነዳችው ፥
፳፮፤ እንደ ፡ አክዓብ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ አልነበረም ። እግ
ዚአብሔር ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ያጠ
ፋቸው ፡ አሞራውያን ፡ እንደ ፡ ሠሩት ፡ ሁሉ ፥
ጣዖታትን ፡ በመከተል ፡ እጅግ ፡ ርኩስ ፡ ነገር ፡
ሠራ ።

፳፯፤ አክዓብም ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ልብ
ሱን ፡ ቀድዶ ፡ ገላውን ፡ ማቅ ፡ አለበሰ ፥ ጾመም ፥
በማቅ ፡ ላይም ፡ ተኛ ፥ ቅስስ ፡ ብሎም ፡ ሄደ ።
፳፰፤፳፱፤ ደግሞም ፡— አክዓብ ፡ በፊቴ ፡ እንደ ፡ ተዋረደ ፡
አየህን ? በፊቴ ፡ የተዋረደ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በልጁ ፡
ዘመን ፡ በቤቱ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አመጣለሁ ፡
እንጂ ፡ በእርሱ ፡ ዘመን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አላመ
ጣም ፡ የሚል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡
ቴስብያዊው ፡ ወደ ፡ ኤልያስ ፡ መጣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩፤ የሶርያም ፡ ንጉሥ ፡ ወልደ ፡ አዴር ፡ ጭፍራ
ውን ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰበ ፤ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ሠላሳ ፡
ሁለት ፡ ነገሥት ፡ ነበሩ ፥ ፈረሶችና ፡ ሰረገሎችም ፡
ነበሩ ፤ ወጥቶም ፡ ሰማርያን ፡ ከበበ ፥ ወጋትም ።
፪፤ ወደ ፡ እስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ አክዓብ ፡—
፫፤ ወልደ ፡ አዴር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ብርህና ፡
ወርቅህ ፡ ለእኔ ፡ ነው ፤ ሴቶችህና ፡ መልከከሞ
ቹም ፡ ልጆችህ ፡ ለእኔ ፡ ናቸው ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡
፬፤ ከተማይቱ ፡ መልእክተኞችን ፡ ላከ ። የእስራኤ
ልም ፡ ንጉሥ ፡ መልሶ ፡— ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥
አንተ ፡ እንዳልህ ፡ ነው ፤ እኔ ፡ ለእኔም ፡ የሆ
፭፤ ነው ፡ ሁሉ ፡ የአንተ ፡ ነው ፡ አለ ። ደግሞም ፡
መልእክተኞች ፡ ተመልሰው ፡— ወልደ ፡ አዴር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— ቀድሞ ፡ ብርህንና ፡ ወርቅ
ህን ፡ ሴቶችህንና ፡ ልጆችህንም ፡ ትሰጠኛለህ ፡
፮፤ ብዬ ፡ ልኬብህ ፡ ነበር ፤ ነገም ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡
ባሪያዎቼን ፡ እልክብሃለሁ ፥ ቤትህንም ፡ የባሪያ
ዎችህንም ፡ ቤቶች ፡ ይበረብራሉ ፤ ደስ ፡ የሚ
ያሰኛቸውንም ፡ ሁሉ ፡ በእጃቸው ፡ አድርገው ፡
ይወስዳሉ ፡ አሉ ።

፯፤ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ የአገሩን ፡ ሽማግሌ
ዎች ፡ ሁሉ ፡ ጠርቶ ፡— ተመልከቱ ፥ ይህም ፡
ሰው ፡ ክፉ ፡ እንዲሻ ፡ እዩ ፤ ስለ ፡ ሴቶቼ ፡ ስለ ፡
ልጆቼ ፡ ስለ ፡ ብሬና ፡ ወርቄም ፡ ላከብኝ ፥ እን
፰፤ ቢም ፡ አላልሁም ፡ አለ ። ሽማግሌዎችም ፡ ሁሉ ፡
ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡— አትስማው ፥ እሺም ፡ አት
፱፤ በለው ፡ አሉት ። ለወልደ ፡ አዴርም ፡ መልእክ
ተኞች ፡— ለጌታዬ ፡ ለንጉሥ ፡— ለእኔ ፡ ለባ
ሪያህ ፡ በመጀመሪያ ፡ የላክህብኝን ፡ ሁሉ ፡ አደ
ርጋለሁ ፤ ይህን ፡ ግን ፡ አደርገው ፡ ዘንድ ፡ አይ
ቻለኝም ፡ በሉት ፡ አላቸው ። መልእክተኞችም ፡
፲፤ ተመልሰው ፡ ይህን ፡ አወሩለት ። ወልደ ፡ አዴ
ርም ፡— ለሚከተለኝ ፡ ሕዝብ ፡ የሰማርያ ፡ ትቢያ ፡
ጭብጥ ፡ ጭብጥ ፡ ይበቃው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ አማ
ልክት ፡ ይህን ፡ ያድርጉብኝ ፡ ይህንም ፡ ይጨም
፲፩፤ ሩብኝ ፡ ብሎ ፡ ላከበት ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡
መልሶ ፡— በቃ ፤ ለሰልፍ ፡ የሚታጠቅ ፡ ጋሻ ፡
ጠፉን ፡ እንደሚያወልቅ ፡ አይመካ ፡ አለው ።
፲፪፤ ወልደ ፡ አዴርም ፡ ያን ፡ ነገር ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ከነ
ገሥታቱ ፡ ጋር ፡ በድንኳኑ ፡ ውስጥ ፡ ይጠጣ ፡
ነበር ፤ ባሪያዎቹንም ፡— ተሰለፉ ፡ አላቸው ፤
እነርሱም ፡ በከተማይቱ ፡ ትይዩ ፡ ተሰለፉ ።

፲፫፤ እነሆም ፥ ነቢይ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ንጉሥ ፡
ወደ ፡ አክዓብ ፡ ቀርቦ ፡— እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፡— ይህን ፡ ብዙ ፡ ጭፍራ ፡ ሁሉ ፡
ታያለህን ? እነሆ ፥ ዛሬ ፡ በእጅህ ፡ አሳልፌ ፡
እሰጠዋለሁ ፥ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡
፲፬፤ ሆንሁ ፡ ታውቃለህ ፡ አለ ። አክዓብም ፡— በማን ?
አለ ፤ እርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— በአውራጆቹ ፡ አለቆች ፡ ጕልማ
ሶች ፡ አለ ፤ እርሱም ፡— ሰልፉን ፡ ማን ፡ ይጀም
ራል ? አለ ፤ እርሱም ፡— አንተ ፡ አለው ።
፲፭፤ የአውራጆቹንም ፡ አለቆች ፡ ጕልማሶች ፡ ቈጠረ ፥
ሁለት ፡ መቶም ፡ ሠላሳ ፡ ሁለት ፡ ነበሩ ፤ ከእነ
ርሱም ፡ በኋላ ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፥ የእስራኤ
ልን ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፥ ቈጠረ ፥ ሰባትም ፡ ሺህ ፡
ነበሩ ።

፲፮፤ ቀትርም ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ወጡ ፤ ወልደ ፡
አዴር ፡ ረዳቶቹም ፡ ሠላሳ ፡ ሁለቱ ፡ ነገሥታት ፡
እየጠጡ ፡ በድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ይሰክሩ ፡ ነበር ።
፲፯፤ የአውራጆቹም ፡ አለቆች ፡ ጕልማሶች ፡ አስ
ቀድመው ፡ ወጡ ፤ ወልደ ፡ አዴርም ፡ መልእክተ
ኞችን ፡ ላከ ፥ እነርሱም ፡— ሰዎች ፡ ከሰማርያ ፡
፲፰፤ ወጥተዋል ፡ ብለው ፡ ነገሩት ። እርሱም ፡—
ለዕርቅ ፡ ወይም ፡ ለሰልፍ ፡ መጥተው ፡ እንደ ፡
፲፱፤ ሆነ ፡ በሕይወታቸው ፡ ያዙአቸው ፡ አለ ። እነ
ዚህም ፡ የአውራጆች ፡ አለቆች ፡ ጕልማሶች ፡
ከከተማይቱ ፡ ወጡ ፥ ሠራዊትም ፡ ተከተላ
፳፤ ቸው ። ሁሉም ፡ በእያንዳንዱ ፡ በፊቱ ፡ የነ
በረውን ፡ ሰው ፡ ገደለ ፥ ሶርያውያንም ፡ ሸሹ ፤
እስራኤልም ፡ አሳደዱአቸው ፥ የሶርያም ፡
ንጉሥ ፡ ወልደ ፡ አዴር ፡ በፈረሱ ፡ አመለጠ ።
፳፩፤ የእስራኤል ፡ ንጉሥም ፡ ወጥቶ ፡ ፈረሶቹንና ፡
ሰረገሎቹን ፡ ያዘ ፥ ሶርያውያንንም ፡ በታላቅ ፡
ውጊት ፡ ገደላቸው ።

፳፪፤ ነቢዩም ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ቀርቦ ፡—
የሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ በሚመጣው ፡ ዓመት ፡ ይመ
ጣብሃልና ፡ ሂድ ፥ በርታ ፥ የምታደርገውንም ፡
፳፫፤ ተመልከትና ፡ እወቅ ፡ አለው ። የሶርያም ፡
ንጉሥ ፡ ባሪያዎች ፡ እንዲህ ፡ አሉት ፡— አምላ
ካቸው ፡ የተራሮች ፡ አምላክ ፡ ነው ፤ ስለዚህ ፡

በርትተውብን ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በሜዳ ፡
ላይ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ብንዋጋ ፡ በእርግጥ ፡ እን
፳፬፤ በረታባቸዋለን ። ይህንም ፡ አድርግ ፤ ከጭፍ
ሮችህ ፡ ነገሥታቱን ፡ አርቅ ÷ በፋንታቸውም ፡
፳፭፤ አለቆችን ፡ ሹም ። አንተም ፡ ቀድሞ ፡ እንደ ፡
ጠፋብህ ፡ ሠራዊት ÷ ፈረሱን ፡ በፈረስ ፡ ፋንታ ÷
ሰረገላውንም ፡ በሰረገላ ፡ ፋንታ ÷ ሠራዊትን ፡
ቍጠር ፤ በሜዳም ፡ ላይ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ እን
ዋጋለን ÷ በእርግጥም ፡ እንበረታባቸዋለን ።
ምክራቸውንም ፡ ሰማ ÷ እንዲሁም ፡ አደረገ ።
፳፮፤ በሚመጣውም ፡ ዓመት ፡ ወልደ ፡ አዴር ፡
ሶርያውያንን ፡ አሰለፈ ÷ ከእስራኤልም ፡ ጋር ፡
፳፯፤ ይዋጋ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ አፌቅ ፡ ወጣ ። የእስራ
ኤልም ፡ ልጆች ፡ ተሰለፉ ÷ ሊገጥሙአቸውም ፡
ወጡ ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ሁለት ፡
ትናንሽ ፡ የፍየል ፡ መንጋዎች ፡ ሆነው ፡ በፊ
ታቸው ፡ ሰፈሩ ፤ ሶርያውያን ፡ ግን ፡ ምድሩን ፡
፳፰፤ ሞልተው ፡ ነበር ። የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡
ቀርቦ ፡ የእስራኤልን ፡ ንጉሥ ፡— እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— ሶርያውያን ፡— እግዚአብ
ሔር ፡ የተራሮች ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
የሸለቆ ፡ አምላክ ፡ አይደለም ፡ ብለዋልና ፡ ይህን ፡
ታላቅ ፡ ጭፍራ ፡ ሁሉ ፡ በእጅህ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጠ
ዋለሁ ÷ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡
፳፱፤ ታውቃላችሁ ፡ አለው ። እነዚህም ፡ በእነዚያ ፡
ትይዩ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ ሰፈሩ ፤ በሰባተኛውም ፡
ቀን ፡ ተጋጠሙ ÷ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከሶር
ያውያን ፡ በአንድ ፡ ቀን ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ እግረኛ ፡
፴፤ ገደሉ ። የቀሩትም ፡ ወደ ፡ አፌቅ ፡ ወደ ፡ ከተ
ማይቱ ፡ ውስጥ ፡ ሸሹ ፤ ቅጥሩም ፡ በቀሩት ፡
በሀያ ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ወደቀ ።
ወልደ ፡ አዴርም ፡ ሸሽቶ ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡
ወደ ፡ እልፍኝ ፡ ውስጥ ፡ ገባ ።
፴፩፤ ባሪያዎቹም ፡— እነሆ ÷ የእስራኤል ፡ ቤት ፡
ነገሥታት ፡ መሐሪዎች ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ሰምተ
ናል ፤ በወገባችን ፡ ማቅ ፡ እንታጠቅ ÷ በራሳች
ንም ፡ ገመድ ፡ እንጠምጥም ÷ ወደ ፡ እስራኤ
ልም ፡ ንጉሥ ፡ እንውጣ ፤ ምናልባት ፡ ነፍስህን ፡
፴፪፤ ይምራታል ፡ አሉት ። ወገባቸውንም ፡ በማቅ ፡
ታጠቁ ÷ በራሳቸውም ፡ ገመድ ፡ ጠመጠሙ ÷
ወደ ፡ እስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ መጥተው ፡— ባሪ
ያህ ፡ ወልደ ፡ አዴር ፡— ነፍሴን ፡ ትምራት ፡
ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ፡ ብሎአል ፡ አሉት ። እር
ሱም ፡— ገና ፡ በሕይወቱ ፡ አለን ? ወንድሜ ፡
፴፫፤ ነው ፡ አለ ። ሰዎቹም ፡ የደግ ፡ ምልክት ፡ አደረ
ጉትና ፡ ቃሉን ፡ ከአፉ ፡ ተቀብለው ፡— ወንድ
ምህ ፡ ወልደ ፡ አዴር ፡ አለ ፡ አሉት ። እርሱም ፡—
ሂዱ ÷ አምጡት ፡ አለ ። ወልደ ፡ አዴርም ፡
ወደ ፡ እርሱ ፡ ወጣ ÷ በሰረገላውም ፡ ላይ ፡ አስ
፴፬፤ ቀመጠው ። ወልደ ፡ አዴርም ፡— አባቴ ፡ ከአ
ባትህ ፡ የወሰዳቸውን ፡ ከተሞች ፡ እመልስልሃ
ለሁ ፤ አባቴ ፡ በሰማርያ ፡ እንዳደረገ ፡ አንተ ፡
በደማስቆ ፡ ገበያ ፡ ታደርጋለህ ፡ አለው ። አክ
ዓብም ፡— እኔም ፡ በዚህ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ እሰድ
ድሃለሁ ፡ አለ ። ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
አድርጎ ፡ ሰደደው ።
፴፭፤ ከነቢያትም ፡ ወገን ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ቃል ፡ ባልንጀራውን ፡— ምታኝ ፡
አለው ። ሰውዮውም ፡ ይመታው ፡ ዘንድ ፡
፴፮፤ እንቢ ፡ አለ ። እርሱም ፡— የእግዚአብሔርን ፡
ቃል ፡ አልሰማህምና ፡ እነሆ ÷ ከእኔ ፡ በራቅህ ፡
ጊዜ ፡ አንበሳ ፡ ይገድልሃል ፡ አለው ። ከእርሱም ፡
በራቀ ፡ ጊዜ ፡ አንበሳ ፡ አግኝቶ ፡ ገደለው ።
፴፯፤ ደግሞም ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ አግኝቶ ፡— ምታኝ ፡
አለው ። ሰውዮውም ፡ መታው ÷ በመምታቱም ፡
፴፰፤ አቈሰለው ። ነቢዩም ፡ ሄዶ ፡ በመንገድ ፡ አጠ
ገብ ፡ ንጉሡን ፡ ቆየው ፤ ዓይኖቹንም ፡ በቀጸላው ፡
፴፱፤ ሸፍኖ ፡ ተሸሸገ ። ንጉሡም ፡ ባለፈ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡
እርሱ ፡ ጮኸ ፡— ባሪያህ ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ መካ
ከል ፡ ወጣ ፤ እነሆም ÷ አንድ ፡ ሰው ፡ ፈቀቅ ፡
ብሎ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ አመጣና ፡—
ይህን ፡ ሰው ፡ ጠብቅ ÷ ቢኰበልልም ፡ ነፍስህ ፡
በነፍሱ ፡ ፋንታ ፡ ትሆናለች ÷ ወይም ፡ አንድ ፡
፵፤ መክሊት ፡ ብር ፡ ትከፍላለህ ፡ አለኝ ። ባሪያ
ህም ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ ሲመለከት ፡ ጠፋ ፡
አለው ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡— ፍርድህ ፡
እንዲሁ ፡ ይሆናል ፤ አንተ ፡ ፈርደኸዋል ፡
፵፩፤ አለው ። ፈጥኖም ፡ ቀጸላውን ፡ ከዓይኑ ፡ አነሣ ፤
የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ከነቢያት ፡ ወገን ፡ እንደ ፡
፵፪፤ ሆነ ፡ አወቀው ። እርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— እኔ ፡ እርም ፡ ያልሁትን ፡
ሰው ፡ ከእጅህ ፡ አውጥተሃልና ፡ ነፍስህ ፡ በነ
ፍሱ ፡ ፋንታ ÷ ሕዝብህም ፡ በሕዝቡ ፡ ፋንታ ፡
፵፫፤ ይሆናሉ ፡ አለው ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ እየ
ተቈጣና ፡ እየተናደደ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመለሰ ÷
ወደ ፡ ሰማርያም ፡ መጣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩፤ ሶርያና ፡ እስራኤልም ፡ ሳይዋጉ ፡ ሦስት ፡
፪፤ ዓመት ፡ ተቀመጡ ። በሦስተኛውም ፡ ዓመት ፡
የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡
፫፤ ንጉሥ ፡ ወረደ ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ባሪ
ያዎቹን ፡— ሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡ የእኛ ፡ እንደ ፡
ሆነች ÷ እኛም ፡ ከሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ ሳንወ
ስዳት ፡ ዝም ፡ እንዳልን ፡ ታውቃላችሁን ? አላ
፬፤ ቸው ። ኢዮሣፍጥንም ፡— በሬማት ፡ ዘገለ
ዓድ ፡ እንዋጋ ፡ ዘንድ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ትመጣለ
ህን ? አለው ። ኢዮሣፍጥም ፡ የእስራኤልን ፡
ንጉሥ ፡— እኔ ፡ እንደ ፡ አንተ ÷ ሕዝቤም ፡ እንደ ፡
ሕዝብህ ÷ ፈረሶቼም ፡ እንደ ፡ ፈረሶችህ ፡ ናቸው ፡
አለው ።
፭፤ ኢዮሣፍጥም ፡ የእስራኤልን ፡ ንጉሥ ፡— የእ
ግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አስቀድመህ ፡ ትጠይቅ ፡
፮፤ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለው ። የእስራኤልም ፡
ንጉሥ ፡ ነቢያቶቹን ፡ አራት ፡ መቶ ፡ የሚያህሉ
ትን ፡ ሰዎች ፡ ሰብስቦ ፡— ወደ ፡ ሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡
ለሰልፍ ፡ ልሂድን ? ወይስ ፡ ልቅር ? አላቸው ።
እነርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡ በንጉሥ ፡ እጅ ፡

አሳልፎ ፡ ይሰጣታልና ፡ ውጣ ፡ አሉት ። ኢዮ
፯ ሣፍጥ ፡ ግን ፡— እንጠይቀው ፡ ዘንድ ፡ ሌላ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ነቢይ ፡ በዚህ ፡ አይገኝምን ?
፰ አለ ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮሣፍጥን ፡—
እግዚአብሔርን ፡ የምንጠይቅበት ፡ የይምላ ፡
ልጅ ፡ ሚክያስ ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ አለ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ እንጂ ፡ መልካም ፡ ትንቢት ፡
አይናገርልኝምና ፡ እጠላዋለሁ ፡ አለው ። ኢዮ
ሣፍጥም ፡— ንጉሥ ፡ እንዲህ ፡ አይበል ፡ አለ ።
፱ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ አንዱን ፡ ጃንደረባ ፡
ጠርቶ ፡— የይምላን ፡ ልጅ ፡ ሚክያስን ፡ ፈጥ
፲ ነህ ፡ አምጣ ፡ አለው ። የእስራኤል ፡ ንጉሥና ፡
የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ ልብሰ ፡ መንግ
ሥት ፡ ለብሰው ፡ በሰማርያ ፡ በር ፡ መግቢያ ፡
አጠገብ ፡ በአደባባይ ፡ በዙፋኖቻቸው ፡ ላይ ፡
ተቀምጠው ፡ ነበር ፤ ነቢያቶቹም ፡ ሁሉ ፡ በፊ
፲፩ ታቸው ፡ ትንቢት ፡ ይናገሩ ፡ ነበር ። የክን
ዓና ፡ ልጅ ፡ ሴዴቅያስም ፡ የብረት ፡ ቀንዶች ፡
ሠርቶ ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
እስኪጠፉ ፡ ድረስ ፡ በእነዚህ ፡ ሶርያውያንን ፡
፲፪ ትወጋለህ ፡ አለ ። ነቢያትም ፡ ሁሉ ፡— እግዚ
አብሔር ፡ በንጉሡ ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣታ
ልና ፡ ወደ ፡ ሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡ ሂድና ፡ ተከና
ወን ፡ እያሉ ፡ እንዲህ ፡ ትንቢት ፡ ይናገሩ ፡ ነበር ።
፲፫ ሚክያስንም ፡ ሊጠራ ፡ የሄደ ፡ መልእክ
ተኛ ፡— እነሆ ፥ ነቢያት ፡ ሁሉ ፡ በአንድ ፡ አፍ ፡
ሆነው ፡ ለንጉሡ ፡ መልካምን ፡ ይናገራሉ ፤ ቃል
ህም ፡ እንደ ፡ ቃላቸው ፡ እንዲሆን ፡ መልካም ፡
፲፬ እንድትናገር ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለው ። ሚክያ
ስም ፡— ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! እግዚአብ
ሔር ፡ የሚነግረኝን ፡ እርሱን ፡ እናገራለሁ ፡
፲፭ አለ ። ወደ ፡ ንጉሡም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሡ ፡—
ሚክያስ ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ ሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡ ለሰ
ልፍ ፡ እንሂድን ? ወይስ ፡ እንቅር ? አለው ፤ እር
ሱም ፡— ውጣና ፡ ተከናወን ፤ እግዚአብሔርም ፡
በንጉሡ ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣታል ፡ ብሎ ፡ መለ
፲፮ ሰለት ። ንጉሡም ፡— ከእውነት ፡ በቀር ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ስም ፡ እንዳትነግረኝ ፡ ስንት ፡ ጊዜ ፡
፲፯ አምልሃለሁ ? አለው ። እርሱም ፡— እስራኤል ፡
ሁሉ ፡ ጠባቂ ፡ እንደሌላቸው ፡ በጎች ፡ በተራሮች ፡
ላይ ፡ ተበትነው ፡ አየሁ ፤ እግዚአብሔርም ፡—
ለእነዚህ ፡ ጌታ ፡ የላቸውም ፡ እያንዳንዱም ፡
በሰላም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ይመለስ ፡ አለ ፡ ብሎ ፡
፲፰ ተናገረ ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮሣፍ
ጥን ፡— ክፉ ፡ እንጂ ፡ መልካም ፡ እንደማይናገ
፲፱ ርልኝ ፡ አላልሁህምን ? አለው ። ሚክያስም ፡
አለ ፡— እንግዲህ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
ስማ ፤ እግዚአብሔር ፡ በዙፋኑ ፡ ተቀምጦ ፥ የሰ
ማይም ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ በቀኙና ፡ በግራው ፡
፳ ቆመው ፡ አየሁ ። እግዚአብሔርም ፡— ወጥቶ ፡
በሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡ ይወድቅ ፡ ዘንድ ፡ አክዓ
ብን ፡ የሚያሳስት ፡ ማን ፡ ነው ? አለ ። አንዱም ፡
እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፥ ሌላውም ፡ እንዲያ ፡ ያለ ፡
፳፩ ነገር ፡ ተናገረ ። መንፈስም ፡ ወጣ ፡ በእግዚአ
ብሔርም ፡ ፊት ፡ ቆሞ ፡— እኔ ፡ አሳስተዋለሁ ፡
፳፪ አለ ። እግዚአብሔርም ፡— በምን ? አለው ፤
እርሱም ፡— ወጥቼ ፡ በነቢያቶቹ ፡ ሁሉ ፡ አፍ ፡
ሐሰተኛ ፡ መንፈስ ፡ እሆናለሁ ፡ አለ ። እግዚአ
ብሔርም ፡— ማሳሳትስ ፡ ታሳስተዋለህ ፥ ይሆን
ልሃልም ፤ ውጣ ፥ እንዲሁም ፡ አድርግ ፡ አለ ።
፳፫ አሁንም ፥ እነሆ ፥ እግዚአብሔር ፡ በእነዚህ ፡
በነቢያትህ ፡ ሁሉ ፡ አፍ ፡ ሐሰተኛ ፡ መንፈስ ፡
አድርጎአል ፤ እግዚአብሔርም ፡ በላይህ ፡ ክፉ ፡
ተናግሮብሃል ።
፳፬ የክንዓናም ፡ ልጅ ፡ ሴዴቅያስ ፡ ቀረበ ፥ ሚክያ
ስንም ፡ ጉንጩን ፡ በጥፊ ፡ መታውና ፡— አንተን ፡
ሊናገር ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ በምን ፡
፳፭ መንገድ ፡ ከእኔ ፡ አለፈ ? አለ ። ሚክያስም ፡—
እነሆ ፥ በዚያ ፡ ቀን ፡ ልትሸሸግ ፡ ወደ ፡ እልፍ
፳፮ ኝህ ፡ በሄድህ ፡ ጊዜ ፡ ታያለህ ፡ አለ ። የእስራኤ
ልም ፡ ንጉሥ ፡— ሚክያስን ፡ ውሰዱ ፥ ወደ ፡
ከተማይቱም ፡ ሹም ፡ ወደ ፡ አሞን ፡ ወደ ፡ ንጉ
ሡም ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢዮአስ ፡ መልሳችሁ ፡—
፳፯ ንጉሡ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በደኅና ፡ እስክመ
ለስ ፡ ድረስ ፡ ይህን ፡ ሰው ፡ በግዞት ፡ አኑሩት ፥
የመከራም ፡ እንጀራ ፡ መግቡት ፥ የመከራም ፡
፳፰ ውኃ ፡ አጠጡት ፡ በሉ ፡ አለ ። ሚክያስም ፡—
በደኅና ፡ ብትመለስ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእኔ ፡ የተ
ናገረ ፡ አይደለም ፡ አለ ። ደግሞም ፡— አሕዛብ ፡
ሁሉ ፡ ሆይ ፥ ስሙኝ ፡ አለ ።
፳፱ የእስራኤልም ፡ ንጉሥና ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡
ኢዮሣፍጥ ፡ ወደ ፡ ሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡ ወጡ ።
፴ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮሣፍጥን ፡— ልብ
ሴን ፡ ለውጬ ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ እገባለሁ ፤ አንተ ፡
ግን ፡ ልብስህን ፡ ልበስ ፡ አለው ። የእስራኤ
ልም ፡ ንጉሥ ፡ ልብሱን ፡ ለውጦ ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡
፴፩ ገባ ። የሶርያም ፡ ንጉሥ ፡ ሠላሳ ፡ ሁለቱን ፡ የሰ
ረገሎች ፡ አለቆች ፡— ከእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡
በቀር ፥ ታናሽ ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ታላቅ ፡ ከማና
ቸውም ፡ ጋር ፡ አትግጠሙ ፡ ብሎ ፡ አዝዞ ፡ ነበር ።
፴፪ የሰረገሎች ፡ አለቆችም ፡ ኢዮሣፍጥን ፡ በዩ ፡
ጊዜ ፡— በእውነት ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ነው ፡
አሉ ፤ ይገጥሙትም ፡ ዘንድ ፡ ከበቡት ፤ ኢዮሣ
፴፫ ፍጥም ፡ ጮኸ ። የሰረገሎች ፡ አለቆችም ፡ የእ
ስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ እንዳልሆነ ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ እር
፴፬ ሱን ፡ ከማሳደድ ፡ ተመለሱ ። አንድ ፡ ሰውም ፡
ቀስቱን ፡ ድንገት ፡ ገትሮ ፡ የእስራኤልን ፡ ንጉሥ ፡
በጥሩሩ ፡ ልብስ ፡ መጋጠሚያ ፡ በኩል ፡ ወጋው ፤
ሰረገለኛውንም ፡— መልሰህ ፡ ንዳ ፥ ተወግቻለ
ሁና ፡ ከሰልፍ ፡ ውስጥ ፡ አውጣኝ ፡ አለው ።
፴፭ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሰልፍ ፡ በረታ ፤ ንጉሡም ፡ በሶ
ርያውያን ፡ ፊት ፡ በሰረገላው ፡ ላይ ፡ ተደግፎ ፡
ነበር ፥ ማታም ፡ ሞተ ፤ የቍስሉም ፡ ደም ፡ በሰ
፴፮ ረገላው ፡ ውስጥ ፡ ፈሰሰ ። በሠራዊቱም ፡ መካ
ከል ፡ ፀሐይ ፡ ስትገባ ፡— ንጉሡ ፡ሞቶአልና ፡
እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ከተማው ፥ እያንዳንዱም ፡
ወደ ፡ አገሩ ፡ ይሂድ ፡ የሚል ፡ ጩኸት ፡ ሆነ ።
፴፯ ወደ ፡ ሰማርያም ፡ መጡ ፥ ንጉሡንም ፡ በሰ

፴፰ ማርያ ፡ ቀበሩት ። አመንዝሮች ፡ በታጠቡበት ፡ በሰማርያ ፡ ኵሬ ፡ ሰረገላውን ፡ አጠቡት ÷ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ ቃል ፡ ውሾች ፡ ደሙን ፡ ላሱት ።
፴፱ የቀረውም ፡ የአክዓብ ፡ ነገር ÷ ያደረገውም ፡ ሁሉ ÷ ከዝሆን ፡ ጥርስም ፡ የሠራው ፡ ቤት ÷ የሠራቸውም ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ÷ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ?
፵ አክዓብም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ÷ በእርሱም ፡ ፋንታ ፡ ልጁ ፡ አካዝያስ ፡ ነገሠ ።

፵፩ አክዓብም ፡ በነገሠ ፡ በአራተኛው ፡ ዓመት ፡ የአሳ ፡ ልጅ ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ነገሠ ።
፵፪ ኢዮሣፍጥ ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሠላሳ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ጎበዝ ፡ ነበረ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። እናቱም ፡ ዓዙባ ፡ የተባለች ፡ የሺልሒ ፡ ልጅ ፡ ነበረች ።
፵፫ በአባቱም ፡ በአሳ ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ ሄደ ÷ ከእርሱም ፡ ፈቀቅ ፡ አላለም ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ አደረገ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በኮረብቶች ፡ ላይ ፡ ያሉትን ፡ መስገጃዎች ፡ አላራቀም ፤ ሕዝቡ ፡ ገና ፡ በኮረብቶቹ ፡ ላይ ፡ ባሉት ፡ መስገጃዎች ፡ ይሠዋና ፡ ያጥን ፡ ነበር ።
፵፬ ኢዮሣፍጥም ፡ ከእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ጋር ፡ ታረቀ ።

፵፭ የቀረውም ፡ የኢዮሣፍጥ ፡ ነገር ÷ የሠራውም ፡ ጭከና ÷ እንዴትም ፡ እንደ ፡ ተወጋ ÷ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ?
፵፮ ከአባቱ ፡ ከአሳ ፡ ዘመን ፡ የተረፉትን ፡ ሰዶማውያን ፡ ከምድር ፡ አጠፋ ።
፵፯ በኤዶምያስም ፡ ንጉሥ ፡ አልነበረም ፤ ሹሙም ፡ እንደ ፡ ንጉሥ ፡ ነበረ ።
፵፰ ኢዮሣፍጥም ፡ ወደ ፡ ኦፌር ፡ ሄደው ፡ ወርቅ ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡ የተርሴስን ፡ መርከቦች ፡ ሠራ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ መርከቦቹ ፡ በዔጽዮንጋብር ፡ ተሰበሩ ፡ እንጂ ፡ አልሄዱም ።
፵፱ የአክዓብም ፡ ልጅ ፡ አካዝያስ ፡ ኢዮሣፍጥን ፡— ባሪያዎቼ ፡ ከባሪያዎችህ ፡ ጋር ፡ በመርከብ ፡ ይሂዱ ፡ አለው ፤ ኢዮሣፍጥ ፡ ግን ፡ አልወደደም ።
፶ ኢዮሣፍጥም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ÷ በአባቱም ፡ በዳዊት ፡ ከተማ ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ተቀበረ ፤ በእርሱም ፡ ፋንታ ፡ ልጁ ፡ ኢዮራም ፡ ነገሠ ።

፶፩ በይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮሣፍጥ ፡ በአሥራ ፡ ሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ የአክዓብ ፡ ልጅ ፡ አካዝያስ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ በሰማርያ ፡ መንገሥ ፡ ጀመረ ፤ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ።
፶፪ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ÷ በአባቱና ፡ በእናቱም ፡ መንገድ ÷ እስራኤልንም ፡ ባሳተው ፡ በናባጥ ፡ ልጅ ፡ በኢዮርብዓም ፡ መንገድ ፡ ሄደ ።
፶፫ በኣልንም ፡ አመለከ ፡ ሰገደለትም ፤ አባቱም ፡ እንዳደረገ ፡ ሁሉ ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አስቈጣ ።

# መጽሐፈ ፡ ነገሥት ፡ ካልዕ ።

( እርሱም ፡ መጽሐፈ ፡ ነገሥት ፡ ራብዕ ፡ ነው ። )

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ አክዓብም ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ሞዓብ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ዐመፀ ።
፪ አካዝያስም ፡ በሰማርያ ፡ በሰገነቱ ፡ ላይ ፡ ሳለ ፡ ከዓይነ ፡ ርግቡ ፡ ወድቆ ፡ ታመመ ፤ እርሱም ፡— ሂዱ ፡ ከዚህም ፡ ደዌ ፡ እድን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የአቃሮንን ፡ አምላክ ፡ ብዔልዜቡልን ፡ ጠይቁ ፡ ብሎ ፡ መልእክተኞችን ፡ ላከ ።
፫ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ቴስብያዊውን ፡ ኤልያስን ፡— ተነሣ ÷ የሰማርያን ፡ ንጉሥ ፡ መልእክተኞች ፡ ለመገናኘት ፡ ውጣና ፡— የአቃሮንን ፡ አምላክ ፡ ብዔልዜቡልን ፡ ትጠይቁ ፡ ዘንድ ፡ የምትሄዱት ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ አምላክ ፡ ስለሌለ ፡ ነውን ?
፬ ስለዚህም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ትሞታለህ ፡ እንጂ ፡ ከወጣህበት ፡ አልጋ ፡ አትወርድም ፡ በላቸው ፡ አለው ። ኤልያስም ፡ ሄደ ።

፭ መልእክተኞችም ፡ ወደ ፡ አካዝያስ ፡ ተመለሱ ÷ እርሱም ፡— ለምን ፡ ተመለሳችሁ ? አላቸው ።
፮ እነርሱም ፡— አንድ ፡ ሰው ፡ ሊገናኘን ፡ መጣና ፡— ሂዱ ÷ ወደ ፡ ላካችሁም ፡ ንጉሥ ፡ ተመልሳችሁ ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የአቃሮንን ፡ አምላክ ፡ ብዔልዜቡልን ፡ ትጠይቅ ፡ ዘንድ ፡ የላክህ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ አምላክ ፡ ስለሌለ ፡ ነውን ? ስለዚህ ፡ ትሞታለህ ፡ እንጂ ፡ ከወጣህበት ፡ አልጋ ፡ አትወርድም ፡ በሉት ፡ አለን ፡ አሉት ።
፯ እርሱም ፡— ሊገናኛችሁ ፡ የወጣው ÷ ይህንስ ፡ ቃል ፡ የነገራችሁ ፡ ሰው ፡ መልኩ ፡ ምን ፡ ይመስላል ? አላቸው ።
፰ እነርሱም ፡— ሰውዮው ፡ ጠጕራም ፡ ነው ÷ በወገቡም ፡ ጠፍር ፡ ታጥቆ ፡ ነበር ፡ አሉት ። እርሱም ፡— ቴስብያዊው ፡ ኤልያስ ፡ ነው ፡ አለ ።

፱ ንጉሡም ፡ የአምሳ ፡ አለቃውን ፡ ከአምሳ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ሰደደ ÷ ወደ ፡ እርሱም ፡ ወጣ ፤ እነሆም ÷ በተራራ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ። እርሱም ፡— የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ሆይ ÷ ንጉሡ ፡— ውረድ ፡ ይልሃል ፡ አለው ።
፲ ኤልያስም ፡ መልሶ ፡ የአምሳ ፡ አለቃውን ፡— እኔስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እሳት ፡ ከሰማይ ፡ ትውረድ ÷ አንተንም ÷ አምሳውንም ፡ ሰዎችህን ፡ ትብላ ፡ አለው ። እሳትም ፡ ከሰማይ ፡ ወርዳ ፡ እርሱንና ፡ አምሳውን ፡ ሰዎቹን ፡ በላች ።
፲፩ ደግሞም ፡ ሌላ ፡ የአምሳ ፡ አለቃ ፡ ከአምሳ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ላከበት ፤ እርሱም ፡— የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ሆይ ÷ ንጉሡ ፡— ፈጥነህ ፡ ውረድ ፡ ይላል ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ።
፲፪ ኤልያስም ፡— እኔስ ፡

የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እሳት ፡ ከሰማይ ፡ ትውረድ ፥ አንተንም ፡ አምሳውንም ፡ ሰዎችህን ፡ ትብላ ፡ አለው ፡፡ የእግዚአብሔርም ፡ እሳት ፡ ከሰማይ ፡ ወርዳ ፡ እርሱንና ፡ አምሳውን ፡ ሰዎቹን ፡ በላች ፡፡ ፲፫ ደግሞም ፡ ሦስተኛ ፡ የአምሳ ፡ አለቃ ፡ ከአምሳ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ሰደደ ፤ ሦስተኛው ፡ የአምሳ ፡ አለቃ ፡ ወጥቶ ፡ በኤልያስ ፡ ፊት ፡ በጒልበቱ ፡ ተንበረከከና ፡— የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ሆይ ፥ ነፍሴና ፡ የእነዚህ ፡ የአምሳው ፡ ባሪያዎችህ ፡ ነፍስ ፡ በፊትህ ፡ የከበረች ፡ ትሁን ፡፡ ፲፬ እነሆ ፥ እሳት ፡ ከሰማይ ፡ ወርዳ ፡ የፊተኞቹን ፡ ሁለቱን ፡ የአምሳ ፡ አለቆችና ፡ አምሳ ፡ አምሳውን ፡ ሰዎቻቸውን ፡ በላች ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ነፍሴ ፡ በፊትህ ፡ የከበረች ፡ ትሁን ፡ ብሎ ፡ ለመነው ፡፡ ፲፭ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ኤልያስን ፡— ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ውረድ ፥ አትፍራውም ፡ አለው ፡፡ ተነሥቶም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወረደ ፡፡ ፲፮ ኤልያስም ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የአቃሮንን ፡ አምላክ ፡ብዔልዜቡልን ፡ ትጠይቅ ፡ ዘንድ ፡ መልእክተኞችን ፡ ልከሃልና ፡ ትሞታለህ ፡ እንጂ ፡ ከወጣህበት ፡ አልጋ ፡ አትወርድም ፡ አለው ፡፡

፲፯ ኤልያስም ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ሞተ ፡፡ ልጅም ፡ አልነበረውምና ፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮሣፍጥ ፡ ልጅ ፡ በኢዮራም ፡ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ ወንድሙ ፡ ኢዮራም ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ፡፡ ፲፰ አካዝያስ ፡ ያደረገው ፡ የቀረው ፡ ነገር ፡ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ?

## ምዕራፍ ፡ ፪ ፡፡

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ እግዚአብሔር ፡ ኤልያስን ፡ በዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ሊያወጣው ፡ በወደደ ፡ ጊዜ ፡ ኤልያስ ፡ ከኤልሳዕ ፡ ጋር ፡ ከጌልገላ ፡ ተነሣ ፡፡ ፪ ኤልያስም ፡ ኤልሳዕን ፡— እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ቤቴል ፡ ልኮኛልና ፡ በዚህ ፡ ቆይ ፡ አለው ፡፡ ኤልሳዕም ፡— ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! በሕያው ፡ ነፍስህም ፡ እምላለሁ ፥ አልለይህም ፡ አለ ፡፡ ወደ ፡ ቤቴልም ፡ ወረዱ ፡፡ ፫ በቤቴልም ፡ የነበሩ ፡ የነቢያት ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ኤልሳዕ ፡ ወጥተው ፡— እግዚአብሔር ፡ ጌታህን ፡ ከራስህ ፡ ላይ ፡ ዛሬ ፡ እንዲወስደው ፡ አውቀሃልን ? አሉት ፡፡ እርሱም ፡— አዎን ፥ አውቄአለሁ ፤ ዝም ፡ በሉ ፡ አላቸው ፡፡ ፬ ኤልያስም ፡— ኤልሳዕ ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ኢያሪኮ ፡ ልኮኛልና ፡ እባክህ ፥ በዚህ ፡ ቆይ ፡ አለው ፡፡ እርሱም ፡— ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! በሕያው ፡ ነፍስህም ፡ እምላለሁ ፥ አልለይህም ፡ አለ ፡፡ ፭ ወደ ፡ ኢያሪኮም ፡ መጡ ፡፡ በኢያሪኮም ፡ የነበሩ ፡ የነቢያት ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ኤልሳዕ ፡ ቀርበው ፡— እግዚአብሔር ፡ ጌታህን ፡ ከራስህ ፡ ላይ ፡ ዛሬ ፡ እንዲወስደው ፡ አውቀሃልን? አሉት ፡፡ እርሱም ፡— አዎን ፥ አውቄአለሁ ፤ ዝም ፡ በሉ ፡ አላቸው ፡፡ ፮ ኤልያስም ፡— እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ልኮኛልና ፡ እባክህ ፥ በዚህ ፡ ቆይ ፡ አለው ፡፡ እርሱም ፡— ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! በሕያው ፡ ነፍስህም ፡ እምላለሁ ፥ አልለይህም ፡ አለ ፡፡ ሁለቱም ፡ ሄዱ ፡፡

፯ ከነቢያትም ፡ ልጆች ፡ አምሳ ፡ ሰዎች ፡ ሄዱ ፥ በፊታቸውም ፡ ርቀው ፡ ቆሙ ፤ እነዚህም ፡ ሁለቱ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ዳር ፡ ቆመው ፡ ነበር ፡፡ ፰ ኤልያስም ፡ መጐናጸፊያውን ፡ ወስዶ ፡ ጠቀለለው ፥ ውኃውንም ፡ መታ ፥ ወዲህና ፡ ወዲያም ፡ ተከፈለ ፤ ሁለቱም ፡ በደረቅ ፡ ተሻገሩ ፡፡ ፱ ከተሻገሩም ፡ በኋላ ፡ ኤልያስ ፡ ኤልሳዕን ፡— ከአንተ ፡ ሳልወሰድ ፡ አደርግልህ ፡ ዘንድ ፡ የምትሻውን ፡ ለምን ፡ አለው ፤ ኤልሳዕም ፡— መንፈስህ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለ ፡፡ ፲ እርሱም ፡— አስቸጋሪ ፡ ነገር ፡ ለምነሃል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ በተወሰድሁ ፡ ጊዜ ፡ ብታየኝ ፡ ይሆንልሃል ፤ አለዚያ ፡ ግን ፡ አይሆንልህም ፡ አለ ፡፡ ፲፩ ሲሄዱም ፥ እያዘገሙም ፡ ሲጫወቱ ፥ እነሆ ፥ የእሳት ፡ ሰረገላና ፡ የእሳት ፡ ፈረሶች ፡ በመካከላቸው ፡ ገብተው ፡ ከፈሉአቸው ፤ ኤልያስም ፡ በዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ወጣ ፡፡

፲፪ ኤልሳዕም ፡ አይቶ ፡— አባቴ ፡ አባቴ ፡ ሆይ ፥ የእስራኤል ፡ ሰረገላና ፡ ፈረሰኞች ፥ ብሎ ፡ ጮኸ ፡፡ ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ አላየውም ፤ ልብሱንም ፡ ይዞ ፡ ከሁለት ፡ ተረተረው ፡፡ ፲፫ ከኤልያስም ፡ የወደቀውን ፡ መጐናጸፊያ ፡ አነሣ ፥ ተመልሶም ፡ በዮርዳኖስ ፡ ዳር ፡ ቆመ ፡፡ ፲፬ ከኤልያስም ፡ የወደቀውን ፡ መጐናጸፊያ ፡ ወስዶ ፡ ውኃውን ፡ መታና ፡— የኤልያስ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወዴት ፡ ነው ? አለ ፤ ውኃውንም ፡ በመታ ፡ ጊዜ ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ ተከፈለ ፤ ኤልሳዕም ፡ ተሻገረ ፡፡

፲፭ ከኢያሪኮም ፡ መጥተው ፡ በአንጻሩ ፡ የነበሩት ፡ የነቢያት ፡ ልጆች ፡ ባዩት ፡ ጊዜ ፡— የኤልያስ ፡ መንፈስ ፡ በኤልሳዕ ፡ ላይ ፡ ዐርፎአል ፡ አሉ ፡፡ ሊገናኙትም ፡ መጥተው ፡ በፊቱ ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ተደፉ ፡፡ ፲፮ እነርሱም ፡— እነሆ ፥ ከባሪያዎችህ ፡ ጋር ፡ አምሳ ፡ ኃያላን ፡ ሰዎች ፡ አሉ ፤ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ አንሥቶ ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ ተራራ ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ ሸለቆ ፡ ጥሎት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ሄደው ፡ ጌታህን ፡ ይፈልጉት ፡ ዘንድ ፡ እንለምንሃለን ፡ አሉት ፡፡ እርሱም ፡— አትስደዱ ፡ አላቸው ፡፡ ፲፯ እስኪያፍርም ፡ ድረስ ፡ ግድ ፡ በሉት ፡ ጊዜ ፡— ስደዱ ፡ አለ ፤ አምሳም ፡ ሰዎች ፡ ሰደዱ ፤ ሦስት ፡ ቀንም ፡ ፈለገው ፡ አላገኙትም ፡፡ ፲፰ በኢያሪኮም ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተመለሱ ፤ እርሱም ፡— አትሂዱ ፡ አላልኋችሁምን ? አላቸው ፡፡

፲፱ የከተማይቱም ፡ ሰዎች ፡ ኤልሳዕን ፡— እነሆ ፥ ጌታችን ፡ እንደምታይ ፡ የዚች ፡ ከተማ ፡ ኑሮ ፡ መልካም ፡ ነው ፤ ውኃው ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ ነው ፥ ምድሪቱም ፡ ፍሬዋን ፡ ትጨነግፋለች ፡ አሉት ፡፡

፳ እርሱም ፦ አዲስ ፡ ማሰሮ ፡ አምጡልኝ ፥ ጨውም ፡ ጨምሩበት ፡ አለ ፤ ያንንም ፡ አመጡለት ። ፳፩ ውኃው ፡ ወዳለበቱም ፡ ምንጭ ፡ ወጥቶ ፡ ጨው ፡ ጣለበትና ፦ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ይህን ፡ ውኃ ፡ ፈውሼዋለሁ ፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ሞትና ፡ ጭንገፋ ፡ አይሆንበትም ፡ አለ ። ፳፪ ኤልሳዕም ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ ነገር ፡ ውኃው ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ተፈውሶአል ።

፳፫ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ቤቴል ፡ ወጣ ፤ በመንገድም ፡ ሲወጣ ፡ ብላቴኖች ፡ ከከተማይቱ ፡ ወጥተው ፦ አንተ ፡ መላጣ ፥ ውጣ ፤ አንተ ፡ መላጣ ፥ ውጣ ፡ ፳፬ ብለው ፡ አፌዙበት ። ዘወርም ፡ ብሎ ፡ አያቸው ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ስም ፡ ረገማቸው ፡ ከዱርም ፡ ሁለት ፡ ድቦች ፡ ወጥተው ፡ ከብላቴኖች ፡ አርባ ፡ ሁለቱን ፡ ሰበበሩአቸው ። ፳፭ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ቀርሜሎስ ፡ ተራራ ፡ ሄደ ፥ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ሰማርያ ፡ ተመለሰ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ በይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮሣፍጥ ፡ በአሥራ ፡ ስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ የአክዓብ ፡ ልጅ ፡ ኢዮራም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ በሰማርያ ፡ መንገሥ ፡ ጀመረ ፥ አሥራ ፡ ሁለትም ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። ፪ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አባቱ ፡ ያሠራውን ፡ የበአልን ፡ ሐውልት ፡ አርቆአልና ፡ እንደ ፡ አባቱና ፡ እንደ ፡ እናቱ ፡ ፫ አልነበረም ። ነገር ፡ ግን ፡ እስራኤልን ፡ ባሳታቸው ፡ በናባጥ ፡ ልጅ ፡ በኢዮርብዓም ፡ ኃጢአት ፡ ተያዘ ፤ ከእርሱም ፡ አልራቀም ።

፬ የሞዓብም ፡ ንጉሥ ፡ ሞሳ ፡ ባለ ፡ በጎች ፡ ነበረ ፤ ለእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ የመቶ ፡ ሺህ ፡ ጠቦትና ፡ የመቶ ፡ ሺህ ፡ አውራ ፡ በጎች ፡ ጠጕር ፡ ይገብ ፭ ርለት ፡ ነበር ። አክዓብም ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ የሞዓብ ፡ ንጉሥ ፡ በእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ላይ ፡ ፮ ዐመፀ ። በዚያም ፡ ጊዜ ፡ ንጉሡ ፡ ኢዮራም ፡ ከሰማርያ ፡ ወጥቶ ፡ እስራኤልን ፡ ሁሉ ፡ አሰለፈ ። ፯ ወደ ፡ ይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ኢዮሣፍጥ ፦ የሞዓብ ፡ ንጉሥ ፡ ዐምፆብኛልና ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ በሞዓብ ፡ ላይ ፡ ለሰልፍ ፡ ትሄዳለህን ? ብሎ ፡ ላከ ። እርሱም ፦ እወጣለሁ ፤ እኔ ፡ እንደ ፡ አንተ ፥ ሕዝቤም ፡ እንደ ፡ ሕዝብህ ፥ ፈረሶቼም ፡ ፰ እንደ ፡ ፈረሶችህ ፡ ናቸው ፡ አለ ። ደግሞም ፦ በምን ፡ መንገድ ፡ እንሄዳለን ? አለ ፤ እርሱም ፦ በኤዶምያስ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ መንገድ ፡ ብሎ ፡ ፱ መለሰ ። የእስራኤል ፡ ንጉሥና ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ የኤዶምያስም ፡ ንጉሥ ፡ ሄዱ ፤ የሰባትም ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ ዞሩ ፤ ለሠራዊቱና ፡ ለተከተሉአቸ ፲ ውም ፡ እንስሶች ፡ ውኃ ፡ አልተገኘም ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፦ ወዮ ! እግዚአብሔር ፡ በሞዓብ ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ እነዚህን ፡ ሦስቱን ፡ ነገሥታት ፡ ጠርቶአልና ፡ ወዮ ፡ ፲፩ አለ ። ኢዮሣፍጥም ፦ በእርሱ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምንጠይቅበት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነቢይ ፡ በዚህ ፡ አይገኝምን ? አለ ። ከእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ባሪያዎች ፡ አንዱ ፦ በኤልያስ ፡ እጅ ፡ ላይ ፡ ውኃ ፡ ያፈስስ ፡ የነበረው ፡ የሣፋጥ ፡ ልጅ ፡ ኤልሳዕ ፡ እዚህ ፡ አለ ፡ ብሎ ፡ መለሰ ። ፲፪ ኢዮሣፍጥም ፦ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ይገኛል ፡ አለ ። የእስራኤል ፡ ንጉሥና ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ የኤዶምያስም ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ወረዱ ።

፲፫ ኤልሳዕም ፡ የእስራኤልን ፡ ንጉሥ ፦ እኔ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አለኝ ? ወደ ፡ አባትህና ፡ ወደ ፡ እናትህ ፡ ነቢያት ፡ ሂድ ፡ አለው ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፦ አይደለም ፥ በሞዓብ ፡ እጅ ፡ ይጥላቸው ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ እነዚህን ፡ ሦስት ፡ ነገሥታት ፡ ጠርቶአል ፡ አለው ። ፲፬ ኤልሳዕም ፦ በፊቱ ፡ የቆምሁት ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! የይሁዳን ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮሣፍጥን ፡ ያላፈርሁ ፡ ብሆን ፡ ኖሮ ፡ አንተን ፡ ባልተመለከትሁና ፡ ባላየሁ ፡ ነበር ። ፲፭ አሁንም ፡ ባለ ፡ በገና ፡ አምጡልኝ ፡ አለ ። ባለ ፡ በገናውም ፡ በደረደረ ፡ ጊዜ ፡ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ መጣችበት ፤ እንዲህም ፡ አለ ፦ ፲፮ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ በዚህ ፡ ሸለቆ ፡ ሁሉ ፡ ጕድጓድ ፡ ቆፈሩ ። ፲፯ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ነፋስ ፡ አታዩም ፥ ዝናብም ፡ አታዩም ፥ ይህ ፡ ሸለቆ ፡ ግን ፡ ውኃ ፡ ይሞላል ፤ እናንተም ፡ ከብቶቻችሁም ፡ እንስሶቻችሁም ፡ ትጠጣላችሁ ። ፲፰ ይህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዓይን ፡ ቀላል ፡ ነገር ፡ ነው ፤ ደግሞም ፡ ሞዓባውያንን ፡ በእጃችሁ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣል ። ፲፱ የተመሸጉትንና ፡ ያማሩትን ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ትመታላችሁ ፥ የሚያፈሩትንም ፡ ዛፎች ፡ ሁሉ ፡ ትቈርጣላችሁ ፥ የውኃውንም ፡ ምንጮች ፡ ሁሉ ፡ ትደፍናላችሁ ፥ መልካሞችንም ፡ እርሻዎች ፡ ሁሉ ፡ በድንጋይ ፡ ታበላሻላችሁ ። ፳ በነጋውም ፡ የቍርባን ፡ ጊዜ ፡ ሲደርስ ፥ እነሆ ፥ ውኃ ፡ በኤዶምያስ ፡ መንገድ ፡ መጣ ፥ ምድሪቱም ፡ ውኃ ፡ ሞላች ።

፳፩ ሞዓባውያንም ፡ ሁሉ ፡ ነገሥታት ፡ ሊወጉአቸው ፡ እንደ ፡ መጡ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ በወገባቸው ፡ ሰይፍ ፡ የሚታጠቁ ፡ ሁሉ ፡ ተሰበሰቡ ፤ ወጥተውም ፡ በአገሩ ፡ ድንበር ፡ ላይ ፡ ቆሙ ። ፳፪ ማልደውም ፡ ተነሡ ፤ ፀሐይም ፡ በውኃው ፡ ላይ ፡ አንጸባረቀ ፥ ሞዓባውያንም ፡ በፊታቸው ፡ ውኃው ፡ እንደ ፡ ደም ፡ ቀልቶ ፡ አዩና ፦ ፳፫ ይህ ፡ ደም ፡ ነው ፤ በእርግጥ ፡ ነገሥታት ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተዋጉ ፥ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ ተጋደሉ ፤ ሞዓብ ፡ ሆይ ፥ እንግዲህ ፡ ወደ ፡ ምርኮህ ፡ ሂድ ፡ አሉ ። ፳፬ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ሰፈር ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ እስራኤላውያን ፡ ተነሥተው ፡ ሞዓባውያንን ፡ መቱ ፥ እነርሱም ፡ ከፊታቸው ፡ ሸሹ ፤ ሞዓባውያንንም ፡ እየመቱ ፡ ወደ ፡ አገሩ ፡ ውስጥ ፡ ገቡ ። ፳፭ ከተሞችንም ፡ አፈረሱ ፤ በመልካሞቹም ፡ እርሻዎች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እስኪሞሉ ፡ ድረስ ፡ እያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ ድንጋይ ፡ ይጥል ፡ ነበር ፤ የውኃውንም ፡ ምንጮች ፡

ሁሉ ፡ ደፈኑ ÷ የሚያፈሩትንም ፡ ዛፎች ፡ ሁሉ ፡ ቈረጡ ፤ የቂርሐራሴትን ፡ ድንጋዮች ፡ ብቻ ፡ አስቀሩ ፤ በለ ፡ ወንጭፎች ፡ ግን ፡ ከበበው ፡ መቱአት ፡፡ ፳፮ የሞዓብም ፡ ንጉሥ ፡ ሰልፍ ፡ እንደ ፡ በረታበት ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ሰይፍ ፡ የሚመዝዙ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ወሰደ ÷ ወደ ፡ ኤዶምያስም ፡ ንጉሥ ፡ ያልፉ ፡ ዘንድ ፡ ሞከሩ ፤ አልቻሉምም ፡፡ ፳፯ በዚያም ፡ ጊዜ ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ንጉሥ ፡ የሚሆነውን ፡ የበኵር ፡ ልጁን ፡ ወስዶ ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ በቅጥሩ ፡ ላይ ፡ አቀረበው ፡፡ በእስራኤልም ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡ ቍጣ ፡ ሆነ ፤ ከዚያም ፡ ርቀው ፡ ወደ ፡ ምድራቸው ፡ ተመለሱ ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፬ ፡፡

፩ ከነቢያትም ፡ ወገን ፡ ሚስቶች ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡— ባሌ ፡ ባሪያህ ፡ ሞቶአል ፤ ባሪያህም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይፈራ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ አንተ ፡ ታውቃለህ ፤ ባለ ፡ ዕዳ ፡ ልጆቼን ፡ ባሪያዎች ፡ አድርጎ ፡ ሊወስዳቸው ፡ መጥቶአል ፡ ብላ ፡ ወደ ፡ ኤልሳዕ ፡ ጮኸች ፡፡ ፪ ኤልሳዕም ፡— አደርግልሽ ፡ ዘንድ ፡ ምን ፡ ትሻለሽ ? በቤትሽ ፡ ያለውን ፡ ንገሪኝ ፡ አላት ፡፡ እርስዋም ፡— ለእኔ ፡ ለባሪያህ ፡ ከዘይት ፡ ማሰሮ ፡ በቀር ፡ በቤቴ ፡ አንዳች ፡ የለኝም ፡ አለች ፡፡ ፫ እርሱም ፡— ሂደሽ ፡ ከጐረቤቶችሽ ፡ ሁሉ ፡ ከሜዳ ፡ ባዶ ፡ ማድጋዎችን ፡ ተዋሺ ፤ አታሳንሺቸውም ፡ አላት ፡፡ ፬ ገብተሽም ፡ ከአንቺና ፡ ከልጆችሽ ፡ በኋላ ፡ በሩን ፡ ዝጊ ÷ ወደ ፡ እነዚህም ፡ ማድጋዎች ፡ ሁሉ ፡ ዘይቱን ፡ ገልብጪ ፤ የሞላውንም ፡ ፈቀቅ ፡ አድርጊ ፡ አለ ፡፡ ፭ እንዲሁም ፡ ከእርሱ ፡ ሄዳ ፡ በሩን ፡ ከእርስዋና ፡ ከልጆችዋ ፡ በኋላ ፡ ዘጋች ፤ እነርሱም ፡ ማድጋዎቹን ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ያመጡ ፡ ነበር ÷ እርስዋም ፡ ትገለብጥ ፡ ነበር ፡፡ ፮ ማድጋዎቹም ፡ በሞሉ ፡ ጊዜ ፡ ልጅዋን ፡— ደግሞ ፡ ማድጋ ፡ አምጣልኝ ፡ አለችው ፤ እርሱም ፡— ሌላ ፡ ማድጋ ፡ የለም ፡ አላት ፤ ዘይቱም ፡ ቆመ ፡፡ ፯ መጥታም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ነገረችው ፤ እርሱም ፡— ሂደሽ ፡ ዘይቱን ፡ ሽጪ ፡ ለባለ ፡ ዕዳውም ፡ ክፈዪ ፤ አንቺና ፡ ልጆችሽም ፡ ከተረፈው ፡ ተመገቡ ፡ አለ ፡፡

፰ አንድ ፡ ቀንም ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ ኤልሳዕ ፡ ወደ ፡ ሱነም ፡ አለፈ ÷ በዚያም ፡ ታላቅ ፡ ሴት ፡ ነበረች ፤ እንጀራ ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ የግድ ፡ አለችው ፤ በዚያም ፡ ባለፈ ፡ ቍጥር ፡ እንጀራ ፡ ሊበላ ፡ ወደዚያ ፡ ይገባ ፡ ነበር ፡፡ ፱ ለባልዋም ፡— ይህ ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ ሁልጊዜ ፡ የሚያልፈው ፡ ቅዱስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አውቃለሁ ፡፡ ፲ ትንሽ ፡ ቤት ፡ በሰገነቱ ፡ ላይ ፡ እንሥራ ፤ በዚያም ፡ አልጋ ፡ ጠረጴዛ ፡ ወንበርና ፡ መቅረዝ ፡ እናኑርለት ፤ ወደ ፡ እኛም ፡ ሲመጣ ፡ ወደዚያ ፡ ይገባል ፡ አለችው ፡፡ ፲፩ አንድ ፡ ቀንም ፡ ወደዚያ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ገብቶ ፡ በዚያ ፡ ዐረፈ ፡፡ ፲፪ ሎሌውንም ፡ ግያዝን ፡— ይህችን ፡ ሱነማዊት ፡ ጥራ ፡ አለው ፡፡ ፲፫ በጠራትም ፡ ጊዜ ፡ በፊቱ ፡ ቆመች ፡፡ እርሱም ፡— እነሆ ÷ ይህን ፡ ሁሉ ፡ አሳብ ፡ አሰብሽልኝ ፤ አሁንስ ፡ ምን ፡ ላድርግልሽ ? ለንጉሥ ፡ ወይስ ፡ ለሠራዊት ፡ አለቃ ፡ ልንገርልሽን ? በላት ፡ አለው ፤ እርስዋም ፡— እኔ ፡ በወገኔ ፡ መካከል ፡ ተቀምጫለሁ ፡ ብላ ፡ መለሰች ፡፡ ፲፬ እርሱም ፡— እንግዲህ ፡ ምን ፡ እናድርግላት ? አለ ፡፡ ግያዝም ፡— ልጅ ፡ የላትም ፤ ባልዋም ፡ ሸምግሎአል ፡ ብሎ ፡ መለሰ ፡፡ ፲፭ እርሱም ፡— ጥራት ፡ አለ ፡፡ በጠራትም ፡ ጊዜ ፡ በደጃፉ ፡ ቆመች ፡፡ ፲፮ እርሱም ፡— በሚመጣው ፡ ዓመት ፡ በዚህ ፡ ወራት ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ትታቀፊአለሽ ፡ አለ ፤ እርስዋም ፡— አይደለም ፤ ጌታዬ ÷ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ሆይ ÷ ባሪያህን ፡ እንዳትዋሻት ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለች ፡፡ ፲፯ ሴቲቱም ፡ ፀነሰች ÷ በዚያም ፡ ወራት ፡ በአዲሱ ፡ ዓመት ፡ ኤልሳዕ ፡ እንዳላት ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፡፡

፲፰ ሕፃኑም ፡ አደገ ÷ አንድ ፡ ቀንም ፡ እህል ፡ አጫጆች ፡ ወዳሉበት ፡ ወደ ፡ አባቱ ፡ ወጣ ፡፡ ፲፱ አባቱንም ፡— ራሴን ፡ ራሴን ፡ አለው ፤ እርሱም ፡ ሎሌውን ፡— ተሸከመህ ፡ ወደ ፡ እናቱ ፡ ውሰደው ፡ አለው ፡፡ ፳ አንሥቶም ፡ ወደ ፡ እናቱ ፡ ወሰደው ፤ በጕልበትዋም ፡ ላይ ፡ እስከ ፡ ቀትር ፡ ድረስ ፡ ተቀመጠ ÷ ሞተም ፡፡ ፳፩ ወጥታም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ አልጋ ፡ ላይ ፡ አጋደመችው ÷ በሩንም ፡ ዘግታበት ፡ ወጣች ፡፡ ፳፪ ባልዋንም ፡ ጠርታ ፡— ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ በፍጥነት ፡ ደርሼ ፡ እመለስ ፡ ዘንድ ፡ አንድ ፡ ሎሌና ፡ አንድ ፡ አህያ ፡ ላክልኝ ፡ አለችው ፡፡ ፳፫ እርሱም ፡— መባቻ ፡ ወይም ፡ ሰንበት ፡ ያይደለ ፡ ዛሬ ፡ ለምን ፡ ትሄጂበታለሽ ? አለ ፡፡ እርስዋም ፡— ደኅና ፡ ነው ፡ አለች ፡፡ ፳፬ አህያውንም ፡ አስጭና ፡ ሎሌዋን ፡— ንዳ ÷ ሂድ ፤ እኔ ፡ ሳላዝዝህ ፡ አታዘግየኝ ፡ አለችው ፡፡

፳፭ እንዲሁም ፡ ሄደች ÷ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ቀርሜሎስ ፡ ተራራ ፡ መጣች ፡፡ የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ ከሩቅ ፡ ባያት ፡ ጊዜ ፡ ሎሌውን ፡ ግያዝን ፡— እነኋት ፡ ሱነማዊቲቱ ፡ መጣች ፤ ፳፮ ተቀበላትም ፡ ዘንድ ፡ ሩጥና ፡— በደኅናሽ ፡ ነውን ? ባልሽ ፡ ደኅና ፡ ነውን ? ልጅሽስ ፡ ደኅና ፡ ነውን ? በላት ፡ አለው ፡፡ እርስዋም ፡— ደኅና ፡ ነው ፡ አለች ፡፡ ፳፯ ወደ ፡ ተራራው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ በመጣች ፡ ጊዜ ፡ እግሮቹን ፡ ጨበጠች ፤ ግያዝም ፡ ሊያርቃት ፡ ቀረበ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡— ነፍስዋ ፡ አዝናለችና ፡ ተዋት ፤ እግዚአብሔርም ፡ ያንን ፡ ከእኔ ፡ ሰውሮታል ፡ አልነገረኝምም ፡ አለ ፡፡ ፳፰ እርስዋም ፡— በውኑ ፡ ከጌታዬ ፡ ልጅን ፡ ለመንሁን ? እኔም ፡— አታታልለኝ ፡ አላልሁህምን ? አለች ፡፡ ፳፱ ግያዝንም ፡— ወገብህን ፡ ታጠቅ ÷ በትሬንም ፡ በእጅህ ፡ ይዘህ ፡ ሂድ ፤ ሰውም ፡ ብታገኝ ፡ ሰላም ፡ አትበል ÷ እርሱም ፡ ሰላም ፡ ቢልህ ፡ አትመልስለት ፤ በትሬንም ፡ በሕፃኑ ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ አኑር ፡ አለው ፡፡ ፴ የሕፃኑም ፡ እናት ፡— ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! በሕያው ፡ ነፍስህም ፡ እምላለሁ ! አልተውህም ፡ አለች ፤ ተነሥቶም ፡ ተከተላት ፡፡ ፴፩ ግያዝም ፡ ቀድሞአቸው ÷ በትሩንም ፡

በሕፃኑ ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ አኖረው ፤ ነገር ፡ ግን ፡
ድምፅ ፡ ወይም ፡ መስማት ፡ አልነበረም ፤ እር
ሱንም ፡ ሊገናኘው ፡ ተመልሶ ፡— ሕፃኑ ፡ አል
ነቃም ፡ ብሎ ፡ ነገረው ።
፴፪፤ ኤልሳዕም ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ እነሆ ÷
ሕፃኑ ፡ ሞቶ ፡ በአልጋው ፡ ላይ ፡ ተጋድሞ ፡
፴፫፤ ነበር ። ገብቶም ፡ በሩን ፡ ከሁለቱ ፡ በኋላ ፡ ዘጋ ÷
፴፬፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ጸለየ ። መጥቶም ፡
በሕፃኑ ፡ ላይ ፡ ተኛ ፤ አፉንም ፡ በአፉ ÷ ዓይኑንም ፡
በዓይኑ ÷ እጁንም ፡ በእጁ ፡ ላይ ፡ አድርጎ ፡ ተጋ
፴፭፤ ደመበት ፤ የሕፃኑም ፡ ገላ ፡ሞቀ ። ተመልሶም ፡
በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡
ተመላለሰ ፤ ደግሞም ፡ ወጥቶ ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡
በሕፃኑ ፡ ላይ ፡ ተጋደመ ፤ ሕፃኑም ፡ ዓይኖቹን ፡
፴፮፤ ከፈተ ። ግያዝንም ፡ ጠርቶ ፡— ይህችን ፡ ሱነ
ማዊት ፡ ጥራ ፡ አለው ። ጠራትም ÷ ወደ ፡ እር
ሱም ፡ በገባች ፡ ጊዜ ፡— ልጅሽን ፡ አንሥተሽ ፡
፴፯፤ ውሰጂ ፡ አላት ። ገብታም ፡ በእግሩ ፡ አጠገብ ፡
ወደቀች ፡ በምድርም ፡ ላይ ፡ ተደፋች ፤ ልጅ
ዋንም ፡ አንሥታ ፡ ወጣች ።
፴፰፤ ኤልሳዕም ፡ ዳግመኛ ፡ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ መጣ ÷
በምድርም ፡ ላይ ፡ ራብ ፡ ነበረ ፤ የነቢያትም ፡
ልጆች ፡ በፊቱ ፡ ተቀምጠው ፡ ነበር ÷ ሎሌው
ንም ፡— ታላቁን ፡ ምንቸት ፡ ጣድ ÷ ለነቢያት ፡
፴፱፤ ልጆችም ፡ ወጥ ፡ ሥራ ፡ አለው ። አንዱም ፡
ቅጠላቅጠል ፡ ያመጣ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፡
ወጣ ÷ የምድረ ፡ በዳውንም ፡ ሐረግ ፡ አገኘ ፡ ከዚ
ያም ፡ የበረሀ ፡ ቅል ፡ ሰበሰበ ÷ ልብሱንም ፡
ሞልቶ ፡ ተመለሰ ÷ መትሮም ፡ በወጡ ፡ ምን
ቸት ፡ ውስጥ ፡ ጨመረው ፤ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
፵፤ ግን ፡ አላወቁም ። ሰዎቹም ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡
ቀዱ ፤ ወጡንም ፡ በቀመሱ ፡ ጊዜ ፡— የእግዚ
አብሔር ፡ ሰው ፡ ሆይ ÷ በምንቸቱ ፡ ውስጥ ፡
ሞት ፡ አለ ፡ ብለው ፡ ጮኹ ፤ ይበሉም ፡ ዘንድ ፡
፵፩፤ አልቻሉም ። እርሱም ፡— ዱቄት ፡ አምጡልኝ ፡
አለ ፤ በምንቸቱም ፡ ውስጥ ፡ ጥሎ ፡— ይበሉ ፡
ዘንድ ፡ ለሕዝቡ ፡ ቅዱ ፡ አለ ። በምንቸቱም ፡
ውስጥ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አልተገኘም ።
፵፪፤ አንድ ፡ ሰውም ፡ ከበኣልሻሊሻ ፡ የበኵራቱን ፡
እንጀራ ÷ ሀያ ፡ የገብስ ፡ እንጀራ ÷ የእህልም ፡
እሸት ፡ በአቁማዳ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ሰው ፡ መጣ ፤ እርሱም ፡— ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ ለሕ
፵፫፤ ዝቡ ፡ ስጣቸው ፡ አለ ። ሎሌውም ፡— ይህን ፡
እንዴት ፡ አድርጌ ፡ ለመቶ ፡ ሰው ፡ እሰጣለሁ ?
አለ ። እርሱም ፡— ይበላሉ ፡ ያተርፉሉም ፡ ብሎ ፡
እግዚአብሔር ፡ ተናግሮአልና ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡
፵፬፤ ለሕዝቡ ፡ ስጣቸው ፡ አለ ። እንዲሁም ፡ በፊታ
ቸው ፡ አኖረው ÷ እንደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡
በሉ ÷ አተረፉም ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ የሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ ሠራዊት ፡ አለቃ ፡ ንዕማ
ንም ፡ እግዚአብሔር ፡ በእርሱ ፡ እጅ ፡ ለሶርያ ፡
ደኅንነትን ፡ ስለ ፡ ሰጠ ፡ በጌታው ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡
ክቡር ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ደግሞም ፡ጽኑዕ ፡ ኃያል ፡
፪፤ ነበረ ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ለምጻም ፡ ነበረ ። ከሶርያው
ያንም ፡ አገር ፡ አደጋ ፡ ጣዮች ፡ ወጥተው ፡ ነበር ÷
ከእስራኤልም ፡ ምድር ፡ ታናሽ ፡ ብላቴና ፡ ሴት ፡
ማርከው ፡ ነበር ፤ የንዕማንንም ፡ ሚስት ፡ ታገለ
፫፤ ግል ፡ ነበር ። እመቤትዋንም ፡— ጌታዬ ፡ በሰማ
ርያ ፡ካለው ፡ ከነቢዩ ፡ ፊት ፡ ቢደርስ ፡ ኖሮ ፡ ከለ
፬፤ ምጹ ፡ በፈወሰው ፡ ነበር ፡ አለቻት ። ንዕማንም ፡
ገብቶ ፡ ለጌታው ፡— ከእስራኤል ፡ አገር ፡ የሆ
ነች ፡ አንዲት ፡ ብላቴና ፡ እንዲህና ፡ እንዲህ ፡
፭፤ ብላለች ፡ ብሎ ፡ ነገረው ። የሶርያም ፡ ንጉሥ ፡
ንዕማንን ፡— ሂድ ÷ ለእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ደብ
ዳቤ ፡ እልካለሁ ፡ አለው ። እርሱም ፡ ሄደ ÷ አሥ
ርም ፡ መክሊት ፡ ብር ÷ ስድስት ፡ ሺህም ፡ ወርቅ ÷
አሥርም ፡ መለወጫ ፡ ልብስ ፡ በእጁ ፡ ወሰደ ።
፮፤ ለእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡— ይህች ፡ ደብዳቤ ፡
ወደ ፡ አንተ ፡ ስትደርስ ፡ ባሪያዬን ፡ ንዕማንን ፡
ከለምጹ ፡ ትፈውሰው ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ሰደድሁ
፯፤ ልህ ፡ እወቅ ፡ የሚል ፡ደብዳቤ ፡ ወሰደ ። የእስ
ራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ደብዳቤውን ፡ ባነበበ ፡ ጊዜ ፡
ልብሱን ፡ ቀድዶ ፡— ሰውን ፡ ከለምጹ ፡ እፈ
ውስ ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መስደዱ ፡
እኔ ፡ በውኑ ፡ ለመግደልና ፡ ለማዳን ፡ የምችል ፡
አምላክ ፡ ሆኜ ፡ ነውን ? ተመልከቱ ÷ የጠብ ፡
ምክንያትም ፡ እንደሚፈልግብኝ ፡ እዩ ፡ አለ ።
፰፤ የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ ኤልሳዕ ፡ የእስራ
ኤል ፡ ንጉሥ ፡ ልብሱን ፡ እንደ ፡ ቀደደ ፡ በሰማ ፡
ጊዜ ፡— ልብስህን ፡ ለምን ፡ ቀደድህ ? ወደ ፡
እኔ ፡ ይምጣ ÷ በእስራኤልም ፡ ዘንድ ፡ ነቢይ ፡
እንዳለ ፡ ያውቃል ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ላከ ።
፱፤ ንዕማንም ፡ በፈረሱና ፡ በሰረገላው ፡ መጣ ÷ በኤ
፲፤ ልሳዕም ፡ ቤት ፡ ደጃፍ ፡ ውጭ ፡ ቆመ ። ኤል
ሳዕም ፡— ሂድ ÷ በዮርዳኖስም ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡
ታጠብ ፤ ሥጋህም ፡ ይፈወሳል ÷ አንተም ፡
ንጹሕ ፡ ትሆናለህ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መልእክ
፲፩፤ ተኛ ፡ ላከ ። ንዕማን ፡ ግን ፡ ተቈጥቶ ፡ ሄደ ÷ እን
ዲህም ፡ አለ ፡— እነሆ ÷ ወደ ፡ እኔ ፡ የሚመጣ ÷
ቆሞም ፡ የአምላኩን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡
የሚጠራ ÷ የለምጹንም ፡ ስፍራ ፡ በእጁ ፡ ዳስሶ ፡
፲፪፤ የሚፈውሰኝ ፡ መስሎኝ ፡ ነበር ። የደማስቆ ፡
ወንዞች ፡ አባናና ፡ ፋርፋ ፡ ከእስራኤል ፡ ውኆች ፡
ሁሉ ፡ አይሻሉምን ? በእነርሱስ ፡ ውስጥ ፡ መታ
ጠብና ፡ መንጻት ፡ አይቻለኝም ፡ ኖሮአልን ?
፲፫፤ ዘወርም ፡ ብሎ ፡ ተቈጥቶ ፡ ሄደ ። ባሪያዎቹም ፡
ቀርበው ፡— አባት ፡ ሆይ ÷ ነቢዩ ፡ ታላቅ ፡ ነገ
ርስ ፡ እንኳ ፡ ቢነግርህ ፡ ኖሮ ፡ ባደረግኸው ፡
ነበር ፤ ይልቁንስ ፡— ታጠብና ፡ ንጹሕ ፡ ሁን ፡
ቢልህ ፡ እንዴት ፡ ነዋ ! ብለው ፡ ተናገሩት ።
፲፬፤ ወረደም ÷ የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ እንደ ፡
ተናገረው ፡ በዮርዳኖስ ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ብቅ ፡
ጥልቅ ፡ አለ ፤ ሥጋውም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ እንደ ፡
ትንሽ ፡ ብላቴና ፡ ሥጋ ፡ ሆኖ ፡ ተመለሰ ÷ ንጹ
ሕም ፡ ሆነ ።
፲፭፤ እርሱም ፡ ከጭፍራው ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡

እግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ተመለሰ ፥ መጥቶም ፡
በፊቱ ፡ ቆመና ፡— እነሆ ፥ ከእስራኤል ፡ ዘንድ ፡
በቀር ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ አምላክ ፡ እንደሌለ ፡
አወቅሁ ፤ አሁንም ፡ ከባሪያህ ፡ በረከት ፡ ትቀበል ፡
ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለ ። ፲፮ ፤ እርሱም ፡— በፊቱ ፡
የቆምሁት ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! አልቀበ
ልም ፡ አለ ። ይቀበለውም ፡ ዘንድ ፡ ግድ ፡ አለው ፤
፲፯ ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ እንቢ ፡ አለ ። ንዕማንም ፡— እኔ ፡
ባሪያህ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
በቀር ፡ ለሌሎች ፡ አማልክት ፡ የሚቃጠል ፡
መሥዋዕት ፡ ወይም ፡ ሌላ ፡ መሥዋዕት ፡ አላቀ
ርብምና ፡ ሁለት ፡ የበቅሎ ፡ ጭነት ፡ አፈር ፡ እን
ድወስድ ፡ እሺ ፡ ትለኝ ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ።
፲፰ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ለእኔ ፡ ለባሪያህ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡
ብቻ ፡ ይቅር ፡ ይበለኝ ፤ ጌታዬ ፡ በዚያ ፡ ይሰግድ ፡
ዘንድ ፡ እጄን ፡ ተደግፎ ፡ ወደ ፡ ሬሞን ፡ ቤት ፡
በገባ ፡ ጊዜ ፥ እኔም ፡ በሬሞን ፡ ቤት ፡ በሰገድሁ ፡
ጊዜ ፥ እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ለእኔ ፡ ለባ
፲፱ ፤ ሪያህ ፡ ይቅር ፡ ይበለኝ ፡ አለ ። እርሱም ፡— በደ
ኅና ፡ ሂድ ፡ አለው ። አንድ ፡ አግድመትም ፡
ያህል ፡ ከእርሱ ፡ ራቀ ።

፳ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ ሎሌ ፡ ግያዝ ፡—
ጌታዬ ፡ ሶርያዊውን ፡ ይህን ፡ ንዕማንን ፡ማረው ፥
ካመጣለትም ፡ ነገር ፡ ምንም ፡ አልተቀበለም ፤
ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! በስተ ፡ ኋላው ፡ እሮ
ጣለሁ ፥ ከእርሱም ፡ አንዳች ፡ እወስዳለሁ ፡ አለ ።
፳፩ ፤ ግያዝም ፡ ንዕማንን ፡ ተከተለው ፤ ንዕማንም ፡
ወደ ፡ እርሱ ፡ ሲሮጥ ፡ ባየው ፡ ጊዜ ፡ ሊገናኘው ፡
ከሰረገላው ፡ ወርዶ ፡— ሁሉ ፡ ደኅና ፡ ነውን ?
፳፪ ፤ አለው ። እርሱም ፡— ደኅና ፡ ነው ፡— አሁን ፡
ከነቢያት ፡ ወገን ፡ የሆኑት ፡ ሁለት ፡ ጕልማሶች ፡
ከተራራማው ፡ ከኤፍሬም ፡ አገር ፡ ወደ ፡ እኔ ፡
መጥተዋል ፤ አንድ ፡ መክሊት ፡ ብርና ፡ ሁለት ፡
መለወጫ ፡ ልብስ ፡ ትሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ እለም
፳፫ ፤ ንሃለሁ ፡ ብሎ ፡ ጌታዬ ፡ ላከኝ ፡ አለ ። ንዕማ
ንም ፡— ሁለት ፡ መክሊት ፡ ትወስድ ፡ ዘንድ ፡
ይፈቀድልህ ፡ አለ ፤ ግድ ፡ አለውም ፤ ሁለቱንም ፡
መክሊት ፡ ብር ፡ በሁለት ፡ ከረጢት ፡ ውስጥ ፡
አሰረና ፡ ከሁለት ፡ መለወጫ ፡ ልብስ ፡ ጋር ፡ ለሁ
ለት ፡ ሎሌዎቹ ፡ አስያዘ ፤ እነርሱም ፡ ተሸክ
፳፬ ፤ መው ፡ በፊቱ ፡ ሄዱ ። ወደ ፡ ከረብታውም ፡
በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ከእጃቸው ፡ ወስዶ ፡ በቤቱ ፡
ውስጥ ፡ አኖራቸው ፤ ሰዎቹንም ፡ አሰናበተ ፥
፳፭ ፤ እነርሱም ፡ ሄዱ ። እርሱ ፡ ግን ፡ ገብቶ ፡ በጌ
ታው ፡ ፊት ፡ ቆመ ፤ ኤልሳዕም ፡— ግያዝ ፡
ሆይ ፥ ከወዴት ፡ መጣህ ? አለው ። እርሱም ፡—
እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ወዴትም ፡ አልሄድሁም ፡ አለ ።
፳፮ ፤ እርሱም ፡— ያ ፡ ሰው ፡ ከሰረገላው ፡ ወርዶ ፡
ሊቀበልህ ፡ በተመለሰ ፡ ጊዜ ፡ ልቤ ፡ ከአንተ ፡
ጋር ፡ አልሄደምን ? ብሩንና ፡ ልብሱን ፥ የወይ
ራውንና ፡ የወይኑን ፡ በታ ፥ በጎችንና ፡ በሬዎ
ችን ፥ ወንዶችንና ፡ ሴቶችን ፡ ባሪያዎች ፡ ትቀ
፳፯ ፤ በል ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ጊዜው ፡ ነውን ? እንግዲ
ህስ ፡ የንዕማን ፡ ለምጽ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፥ ለዘላ
ለምም ፡ በዘርህ ፡ ላይ ፡ ይጣበቃል ፡ አለው ።
እንደ ፡ በረዶም ፡ ለምጻም ፡ ሆኖ ፡ ከእርሱ ፡
ዘንድ ፡ ወጣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ፤ የነቢያትም ፡ ልጆች ፡ ኤልሳዕን ፡— እነሆ ፥
በፊትህ ፡ የምንቀመጥበት ፡ ስፍራ ፡ ጠብቦናል ።
፪ ፤ ወደ ፡ ዮርዳኖስም ፡ እንሂድ ፥ ከእኛም ፡ እያንዳ
ንዱ ፡ ከዚያ ፡ ምሰሶ ፡ ያምጣ ፥ የምንቀመጥበት
ንም ፡ ስፍራ ፡ በዚያ ፡ እንሥራ ፡ አሉት ፤ እር
፫ ፤ ሱም ፡— ሂዱ ፡ አለ ። ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡—
አንተ ፡ ደግሞ ፡ ከእኛ ፡ ከባሪያዎችህ ፡ ጋር ፡ ለመ
ሄድ ፡ ፍቀድ ፡ አለ ። እርሱም ፡— እሄዳለሁ ፡
፬ ፤ አለ ። ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ሄደ ፤ ወደ ፡ ዮርዳኖ
፭ ፤ ስም ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ እንጨት ፡ ቈረጡ ። ከእነ
ርሱም ፡ አንዱ ፡ ምሰሶውን ፡ ሲቈርጥ ፡ የምሳሩ ፡
ብረት ፡ ወደ ፡ ውኃው ፡ ውስጥ ፡ ወደቀ ፤ እር
ሱም ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ ወየው ! ወየው ! የተ
፮ ፤ ዋስሁት ፡ ነበረ ፡ ብሎ ፡ ጮኸ ። የእግዚአብሔ
ርም ፡ ሰው ፡— የወደቀው ፡ ወዴት ፡ ነው ? አለ ፤
ስፍራውንም ፡ አሳየው ፤ እንጨትም ፡ ቈርጦ ፡
፯ ፤ በዚያ ፡ ጣለው ፥ ብረቱም ፡ ተንሳፈፈ ። እር
ሱም ፡— ውሰደው ፡ አለ ፤ እጁንም ፡ ዘርግቶ ፡
ወሰደው ።

፰ ፤ የሶርያም ፡ ንጉሥ ፡ ከእስራኤል ፡ ጋር ፡ ይዋጋ ፡
ነበር ፤ ከባሪያዎቹም ፡ ጋር ፡ ተማክሮ ፡— በዚህ ፡
፱ ፤ ተደብቀን ፡ እንሰፍራለን ፡ አለ ። የእግዚአብሔ
ርም ፡ ሰው ፡— ሶርያውያን ፡ በዚያ ፡ ተደብቀ
ዋልና ፡ በዚያ ፡ ስፍራ ፡ እንዳታልፍ ፡ ተጠን
ቀቅ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ላከ ።
፲ ፤ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡
ወደ ፡ ነገረው ፡ ስፍራ ፡ ሰደደ ፤ አንድ ፡ ጊዜም ፡
ሳይሆን ፥ ሁለት ፡ ጊዜም ፡ ሳይሆን ፡ በዚያ ፡
፲፩ ፤ ራሱን ፡ አዳነ ። የሶርያም ፡ ንጉሥ ፡ ልብ ፡ ስለ
ዚህ ፡ እጅግ ፡ ታወከ ፤ ባሪያዎቹንም ፡ ጠርቶ ፡—
ከእኛ ፡ ዘንድ ፡ ከእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ጋር ፡ የተ
ወዳጀ ፡ እንዳለ ፡ አትነግሩኝምን ? አላቸው ።
፲፪ ፤ ከባሪያዎቹም ፡ አንዱ ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ እንዲህ ፡
እኮ ፡ አይደለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በእልፍኝህ ፡
ውስጥ ፡ ሆነህ ፡ የምትናገረውን ፡ በእስራኤል ፡
ዘንድ ፡ ያለ ፡ ነቢይ ፡ ኤልሳዕ ፡ ለእስራኤል ፡
፲፫ ፤ ንጉሥ ፡ ይነግረዋል ፡ አለ ። እርሱም ፡— ልኬ ፡
አስይዘው ፡ ዘንድ ፡ ሄዳችሁ ፡ ወዴት ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ እዩ ፡ አለ ። እነርሱም ፡— እነሆ ፥ በዶታ
ይን ፡ አለ ፡ ብለው ፡ ነገሩት ።
፲፬ ፤ ወደዚያም ፡ ፈረሶችንና ፡ ሰረገሎችን ፡ እጅ
ግም ፡ ጭፍራ ፡ ሰደደ ፤ በሌሊትም ፡ መጥተው ፡
፲፭ ፤ ከተማይቱን ፡ ከበቡ ። የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡
ሎሌ ፡ ማለዳ ፡ ተነሥቶ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፥ እነሆ ፥ በከ
ተማይቱ ፡ ዙሪያ ፡ ጭፍራና ፡ ፈረሶች ፡ ሰረገሎ
ችም ፡ ነበሩ ። ሎሌውም ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ ወዮ !
፲፮ ፤ ምን ፡ እናደርጋለን ? አለው ። እርሱም ፡—
ከእኛ ፡ ጋር ፡ ያሉት ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ካሉት ፡
፲፯ ፤ ይበልጣሉና ፡ አትፍራ ፡ አለው ። ኤልሳዕም ፡—

አቤቱ ፥ ያይ ፡ ዘንድ ፡ ዓይኖቹን ፥ እባክህ ፥ ግለጥ ፡
ብሎ ፡ ጸለየ ። እግዚአብሔርም ፡ የብላቴናውን ፡
ዓይኖች ፡ ገለጠ ፥ አየም ፤ እነሆም ፥ በኤልሳዕ ፡
ዙሪያ ፡ ያሉት ፡ የእሳት ፡ ፈረሶችና ፡ ሰረገሎች ፡
፲፰ ተራራውን ፡ ሞልተውት ፡ ነበር ። ወደ ፡ እር
ሱም ፡ በወረዱ ፡ ጊዜ ፡ ኤልሳዕ ፡— ይህን ፡ ሕዝብ ፡
ዕውር ፡ ታደርገው ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ፡ ብሎ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸለየ ። ኤልሳዕም ፡ እንደ ፡
፲፱ ተናገረው ፡ ቃል ፡ ዕውር ፡ አደረጋቸው ። ኤል
ሳዕም ፡— መንገዱ ፡ በዚህ ፡ አይደለም ፥ ከተማ
ይቱም ፡ ይህች ፡ አይደለችም ፤ የምትሹትን ፡
ሰው ፡ አሳያችሁ ፡ ዘንድ ፡ ተከተሉኝ ፡ አላቸው ፤
ወደ ፡ ሰማርያም ፡ መራቸው ።

፳ ወደ ፡ ሰማርያም ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ ኤልሳዕ ፡—
አቤቱ ፥ ያዩ ፡ ዘንድ ፡ የእነዚህን ፡ ሰዎች ፡ ዓይኖች ፡
ግለጥ ፡ አለ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዓይኖቻቸውን ፡
ገለጠ ፥ እነርሱም ፡ አዩ ። እነሆም ፥ በሰማርያ ፡
፳፩ መካከል ፡ ነበሩ ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ባያ
ቸው ፡ ጊዜ ፡ ኤልሳዕን ፡— አባቴ ፡ ሆይ ፥ ልግደ
፳፪ ላቸውን ? ልግደላቸውን ? አለው ። እርሱም ፡—
አትግደላቸው ፤ በሰይፍህና ፡ በቀስትህ ፡ የማረ
ክኸውን ፡ ትገድል ፡ ዘንድ ፡ ይገባሃልን ? እንጀ
ራና ፡ ውኃ ፡ በፊታቸው ፡ አኑርላቸው ፥ በልተ
ውና ፡ ጠጥተውም ፡ ወደ ፡ ጌታቸው ፡ ይሂዱ ፡
፳፫ አለው ። ብዙም ፡ መብል ፡ አዘጋጀላቸው ፤ በበ
ሉና ፡ በጠጡ ፡ ጊዜም ፡ አሰናበታቸው ፥ እነር
ሱም ፡ ወደ ፡ ጌታቸው ፡ ሄዱ ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡
የሶርያ ፡ አደጋ ፡ ጣዮች ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ አገር ፡
አልመጡም ።

፳፬ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ ወልደ ፡
አዴር ፡ ሠራዊቱን ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰበ ፥ ወጥቶም ፡
፳፭ ሰማርያን ፡ ከበበት ። በሰማርያም ፡ ታላቅ ፡ ራብ ፡
ሆኖ ፡ ነበር ፤ እነሆም ፥ የአህያ ፡ ራስ ፡ በአምሳ ፡
ብር ፥ የርግብም ፡ ኵስ ፡ የጎሞር ፡ ስምንተኛ ፡
የሚሆን ፡ በአምስት ፡ ብር ፡ እስኪሸጥ ፡ ድረስ ፡
፳፮ ከበቡአት ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ በቅጥር ፡
ላይ ፡ በተመላለሰ ፡ ጊዜ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡—
ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ እርዳኝ ፡ ብላ ፡ ወደ ፡
፳፯ እርሱ ፡ ጮኸች ። እርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡
ያልረዳሽን ፡ እኔ ፡ እንዴት ፡ እረዳሻለሁ ? ከአ
ውድማው ፡ ወይስ ፡ ከመጥመቂያው ፡ ነውን ?
፳፰ አለ ። ንጉሡም ፡— ምን ፡ ሆነሻል ? አላት ፤
እርስዋም ፡— ይህች ፡ ሴት ፡— ዛሬ ፡ እንድን
በላው ፡ ልጅሽን ፡ አምጪ ፤ ነገም ፡ ልጄን ፡
፳፱ እንበላለን ፡ አለችኝ ። ልጄንም ፡ቀቅለን ፡ በላ
ነው ፤ በማግሥቱም ፡— እንድንበላው ፡ ልጅ
ሽን ፡ አምጪ ፡ አልኋት ፤ ልጅዋንም ፡ ሸሸገ
፴ ችው ፡ ብላ ፡ መለሰችለት ። ንጉሡም ፡ የሴቲ
ቱን ፡ ቃል ፡ ሰምቶ ፡ ልብሱን ፡ ቀደደ ፤ በቅጥ
ርም ፡ ይመላለስ ፡ ነበር ፤ ሕዝቡም ፡ በስተ ፡
ውስጥ ፡ በሥጋው ፡ ላይ ፡ ለብሶት ፡ የነበረውን ፡
፴፩ ማቅ ፡ አዩ ። ንጉሡም ፡— የሣፋጥ ፡ ልጅ ፡ የኤ
ልሳዕ ፡ ራስ ፡ ዛሬ ፡ በላዩ ፡ ያደረ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ያድርግብኝ ፥ ይህንም ፡
ይጨምርብኝ ፡ አለ ።

፴፪ ኤልሳዕ ፡ ግን ፡ በቤቱ ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ፥ ሽማ
ግሌዎችም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተቀምጠው ፡ ነበር ፤
ንጉሡ ፡ ሰው ፡ ላከ ፤ መልእክተኛውም ፡ ገና ፡
ሳይደርስ ፡ ለሽማግሌዎች ፡— ይህ ፡ የነፍሰ ፡
ገዳይ ፡ ልጅ ፡ ራሴን ፡ ይቈርጥ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡
ላከ ፡ እዩ ፤ መልእክተኛውም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡
ደጁን ፡ ዘግታችሁ ፡ ከልክሉት ፤ የጌታው ፡ የእ
፴፫ ግሩ ፡ ኮቴ ፡ በኋላው ፡ ነው ፡ አላቸው ። ሲናገ
ራቸውም ፡ መልእክተኛው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡
ደረሰ ፤ እርሱም ፡— እነሆ ፥ ይህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ፥ እግዚአብሔ
ርን ፡ ገና ፡ እጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ምንድር ፡ ነኝ ? አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ኤልሳዕም ፡— የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
ስሙ ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ነገ ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ በሰማርያ ፡ በር ፡ አንድ ፡ መስ
ፈሪያ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ በአንድ ፡ ሰቅል ፥
ሁለትም ፡ መስፈሪያ ፡ ገብስ ፡ በአንድ ፡ ሰቅል ፡
፪ ይሸመታል ፡ አለ ። ንጉሡም ፡ በእጁ ፡ ተደግፎ ፡
የነበረ ፡ አለቃ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ መልሶ ፡—
እነሆ ፥ እግዚአብሔር ፡ በሰማይ ፡ መስኮቶች ፡
ቢያደርግ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ይሆናልን ? አለው ።
እርሱም ፡— እነሆ ፥ በዓይኖችህ ፡ ታየዋለህ ፥
ከዚያም ፡ አትቀምስም ፡ አለ ።

፫ በበሩም ፡ መግቢያ ፡ አራት ፡ ለምጻም ፡ ሰዎች ፡
ነበሩ ፤ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡— እስክንሞት ፡
፬ ድረስ ፡ በዚህ ፡ ለምን ፡ እንቀመጣለን ? ወደ ፡
ከተማ ፡ እንገባ ፡ ዘንድ ፡ ብንወድድ ፡ ራብ ፡ በከ
ተማ ፡ አለ ፥ በዚያም ፡ እንሞታለን ፤ በዚህም ፡
ብንቀመጥ ፡ እንሞታለን ። እንግዲህ ፡ ኑ ፥ ወደ ፡
ሶርያውያን ፡ ሰፈር ፡ እንሽሽ ፤ በሕይወት ፡ ቢያኖ
ሩን ፡ እንኖራለን ፤ ቢገድሉንም ፡ እንሞታለን ፡
፭ ተባባሉ ። ጨለምለም ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሶር
ያውያን ፡ ሰፈር ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ተነሡ ፤ ወደ ፡
ሶርያውያንም ፡ ሰፈር ፡ መጀመሪያ ፡ ዳርቻ ፡
በመጡ ፡ ጊዜ ፥ እነሆ ፥ ማንም ፡ አልነበረም ።
፮ እግዚአብሔር ፡ ለሶርያውያን ፡ የሰረገላና ፡ የፈ
ረስ ፡ የብዙም ፡ ጭፍራ ፡ ድምፅ ፡ አሰምቶ ፡
ነበር ፤ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡— እነሆ ፥ የእስራ
ኤል ፡ ንጉሥ ፡ የኬጢያውያንንና ፡ የግብጻውያ
ንን ፡ ነገሥት ፡ ቀጥሮ ፡ አምጥቶብናል ፡ ይባባሉ ፡
፯ ነበር ። ስለዚህም ፡ ተነሥተው ፡ በጨለማ ፡
ሸሹ ፤ ድንኳኖቻቸውንና ፡ ፈረሶቻቸውን ፡ አህ
ዮቻቸውንና ፡ ሰፈሩን ፡ እንዳለ ፡ ትተው ፡ ነፍ
፰ ሳቸውን ፡ ያድኑ ፡ ዘንድ ፡ ሸሹ ። እነዚህም ፡
ለምጻሞች ፡ ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ መጀመሪያ ፡ ዳርቻ ፡
በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ ድንኳን ፡ ገብተው ፡
በሉ ፡ ጠጡም ፥ ከዚያም ፡ ወርቅና ፡ ብር ፡ ልብ
ስም ፡ ወሰዱ ፥ ሄደውም ፡ ሸሸጉት ፤ ተመልሰ
ውም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ድንኳን ፡ ገቡ ፥ ከዚያም ፡
ደግሞ ፡ ወስደው ፡ ሸሸጉ ።
፱ ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡— መል

ክም ፡ አላደረግንም ፤ ዛሬ ፡ የመልካም ፡ ምስራች ፡
ቀን ፡ ነው ÷ እኛም ፡ ዝም ፡ ብለናል ! እስኪነ
ጋም ፡ ድረስ ፡ ብንቆይ ፡ በደለኞች ፡ እንሆናለን ፤
ኑ ÷ እንሂድ ፤ ለንጉሥ ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፡ እንናገር ፡
፲ ተብባሉ ። መጥተውም ፡— ወደ ፡ ሶርያውያን ፡
ሰፈር ፡ መጣን ÷ እነሆም ÷ ፈረሶችና ፡ አህዮች ፡
ታስረው ÷ ድንኳኖችም ፡ ተተክለው ፡ ነበር ፡
እንጂ ፡ ሰው ፡ አልነበረም ÷ የሰውም ፡ ድምፅ ፡
አልነበረም ፡ ብለው ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ ደጅ ፡
፲፩ ጠባቂ ፡ ጮኹ ። የደጁም ፡ ጠባቂዎች ፡ ጠሩ ÷
፲፪ ለንጉሡም ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ አወሩ ። ንጉሡም ፡
በሌሊት ፡ ተነሥቶ ፡ ባሪያዎቹን ፡— ሶርያውያን ፡
ያደረጉብንን ፡ እነግራችኋለሁ ፤ እንደ ፡ ተራ
ብን ፡ ያውቃሉ ፤ ስለዚህ ፡— ከከተማይቱ ፡
በወጡ ፡ ጊዜ ፡ በሕይወታቸው ፡ እንይዛቸዋለን ÷
ወደ ፡ ከተማም ፡ እንገባለን ፡ ብለው ፡ በሜዳ ፡
ይሸሸጉ ፡ ዘንድ ፡ ከሰፈሩ ፡ ወጥተዋል ፡ አላ
፲፫ ቸው ። ከባሪያዎቹም ፡ አንዱ ፡ መልሶ ፡— በከ
ተማ ፡ ከቀሩት ፡ ፈረሶች ፡ አምስት ፡ ይውሰዱ ፤
እነሆ ÷ እንደ ፡ ቀሩት ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ ወገን ፡
ሁሉ ፡ ናቸው ፤ እነሆ ÷ እንዳለቁ ፡ እንደ ፡ እስራ
ኤል ፡ ወገን ፡ ሁሉ ፡ ናቸው ፤ እንስደድም ÷
፲፬ እንይም ፡ አለ ። ሁለትም ፡ ሰረገሎች ፡ ከፈረ
ሶች ፡ ጋር ፡ ወሰዱ ፤ ንጉሡም ፡— ሄዳችሁ ፡
እዩ ፡ ብሎ ፡ ከሶርያውያን ፡ ሠራዊት ፡ በኋላ ፡
፲፭ ላከ ። በኋላቸው ፡ እስከ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ድረስ ፡
ሄዱ ፤ እነሆም ÷ ሶርያውያን ፡ ሲሸሹ ፡ የጣሉት ፡
ልብስና ፡ ዕቃ ፡ መንገዱን ፡ ሁሉ ፡ ሞልቶ ፡
ነበር ። መልእክተኞችም ፡ ተመልሰው ፡ ለንጉሡ ፡
ነገሩት ።

፲፮ ሕዝቡም ፡ ወጥቶ ፡ የሶርያውያንን ፡ ሰፈር ፡
በዘበዘ ፤ እንደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ አንድ ፡
መስፈሪያ ፡ መልካም ፡ ዱቄት ፡ በአንድ ፡ ሰቅል ÷
ሁለትም ፡ መስፈሪያ ፡ ገብስ ፡ በአንድ ፡ ሰቅል ፡
፲፯ ተሸመተ ። ንጉሡም ፡ ያን ፡ እጁን ፡ ይደግፈው ፡
የነበረውን ፡ አለቃ ፡ በሩን ፡ ይጠብቅ ፡ ዘንድ ፡
አቆመው ። ሕዝቡም ፡ በበሩ ፡ ረገጠው ÷ ንጉ
ሡም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ በወረደ ፡ ጊዜ ፡ የእግዚ
አብሔር ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ ሞተ ።
፲፰ የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ ለንጉሡ ፡— ነገ ፡
በዚህ ፡ ጊዜ ፡ በሰማርያ ፡ በር ፡ ሁለት ፡ መስፈሪያ ፡
ገብስ ፡ በአንድ ፡ ሰቅል ÷ አንድም ፡ መስፈሪያ ፡
መልካም ፡ ዱቄት ፡ በአንድ ፡ ሰቅል ፡ ይሸመታል ፡
ብሎ ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ ነገር ፡ እንዲሁ ፡ ሆነ ።
፲፱ ያም ፡ አለቃ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ መልሶ ፡—
እነሆ ÷ እግዚአብሔር ፡ በሰማይ ፡ መስኮቶች ፡
ቢያደርግ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ይሆናልን ? ብሎ ፡ ነበር ፤
እርሱም ፡— እነሆ ÷ በዓይኖችህ ፡ ታየዋለህ ÷
፳ ከዚያም ፡ አትቀምስም ፡ ብሎት ፡ ነበር ። እን
ዲሁም ፡ ደረሰበት ፤ ሕዝቡም ፡ በበሩ ፡ ረገጠ
ውና ፡ ሞተ ።

ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ ኤልሳዕም ፡ ልጅዋን ፡ ያስነሣላትን ፡ ሴት ፡—
አንቺ ፡ ከቤተ ፡ ሰብሽ ፡ ጋር ፡ ተነሥተሽ ፡ ሂጂ ÷
በምታገኚውም ፡ስፍራ ፡ ተቀመጪ ፤ እግዚአ
ብሔር ፡ ራብ ፡ ጠርቶአል ፤ ሰባት ፡ ዓመትም ፡
በምድር ፡ ላይ ፡ ይመጣል ፡ ብሎ ፡ ተናገራት ።
፪ ሴቲቱም ፡ ተነሥታ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ሰው ፡ ቃል ፡ አደረገች ፤ ከቤተ ፡ ሰብዋም ፡ ጋር ፡
ሄዳ ፡ በፍልስጥኤም ፡ አገር ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡
፫ ተቀመጠች ። ሰባቱም ፡ ዓመት ፡ በተፈጸመ ፡
ጊዜ ፡ ሴቲቱ ፡ ከፍልስጥኤም ፡ አገር ፡ ተመለ
ሰች ፤ ስለ ፡ ቤትዋና ፡ ስለ ፡ መሬትዋ ፡ ልት
፬ ጮኽ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወጣች ። ንጉሡም ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ሎሌ ፡ ከግያዝ ፡ ጋር ፡—
ኤልሳዕ ፡ ያደረገውን ፡ ተአምራት ፡ ሁሉ ፡ ንገ
፭ ረኝ ፡ እያለ ፡ ይጫወት ፡ ነበር ። እርሱም ፡
የሞተውን ፡ እንደ ፡ አስነሣ ፡ ለንጉሡ ፡ ሲና
ገር ÷ እነሆ ÷ ልጅዋን ፡ ያስነሣላት ፡ ሴት ፡
ስለ ፡ ቤትዋና ፡ ስለ ፡ መሬትዋ ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡
ጮኸች ፤ ግያዝም ፡— ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ÷
ሴቲቱ ፡ ይህች ፡ ናት ÷ ኤልሳዕም ፡ ያስነሣው ፡
፮ ልጅዋ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አለ ። ንጉሡም ፡ ሴቲቱን ፡
ጠየቀ ÷ ነገረችውም ። ንጉሡም ፡— የነበረላ
ትን ፡ ሁሉ ÷ መሬትዋንም ፡ ከተወች ፡ ጀምራ ፡
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ያለውን ፡ የእርሻዋን ፡ ፍሬ ፡
ሁሉ ፡ መልስላት ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ እርስዋ ፡ ጃንደ
ረባውን ፡ እዘዘ ።

፯ ኤልሳዕም ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ መጣ ፤ የሶርያም ፡
ንጉሥ ፡ ወልደ ፡ አዴር ፡ ታምሞ ፡ ነበር ፤ ወሬ
ኞችም ፡— የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ወደዚህ ፡
፰ መጥቶአል ፡ ብለው ፡ ነገሩት ። ንጉሡም ፡ አዛ
ሄልን ፡— ገጸ ፡ በረከት ፡ በእጅህ ፡ ወስደህ ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ሰው ፡ ልትገናኝ ፡ ሂድ ፤ በእር
ሱም ፡ አፍ ፡— ከዚህ ፡ በሽታ ፡ እድናለሁን ?
፱ ብለህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠይቅ ፡ አለው ። አዛ
ሄልም ፡ ሊገናኘው ፡ ሄደ ÷ ከእርሱም ፡ ጋር ፡
ከደማስቆ ፡ መልካሙን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ የአርባ ፡
ግመል ፡ ጭነት ፡ ገጸ ፡ በረከት ፡ ወሰደ ፤ መጥ
ቶም ፡ በፊቱ ፡ ቆመና ፡— ልጅህ ፡ የሶርያ ፡
ንጉሥ ፡ ወልደ ፡ አዴር ፡— ከዚህ ፡ በሽታ ፡ እድ
ናለሁን ? ሲል ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ልኮኛል ፡ አለ ።
፲ ኤልሳዕም ፡— ሂድ ፡— መዳንስ ፡ ትድናለህ ፡
በለው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እንዲሞት ፡ እግዚአብሔር ፡
፲፩ አሳይቶኛል ፡ አለው ። እስኪያፍርም ፡ ድረስ ፡
ትኵር ፡ ብሎ ፡ ተመለከተው ፤ የእግዚአብሔርም ፡
፲፪ ሰው ፡ አነባ ። አዛሄልም ፡— ጌታዬ ፡ ለምን ፡
ያነባል ? አለ ። እርሱም ፡— በእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ላይ ፡ የምታደርገውን ፡ ክፋት ፡ ስለማውቅ ፡
ነው ፤ ምሽጎቻቸውን ፡ በእሳት ፡ ታቃጥላለህ ÷
ጕልማሶቻቸውንም ፡ በሰይፍ ፡ ትገድላለህ ÷

ሕፃናቶቻቸውንም ፡ ትፈጠፍጣለህ ÷ እርጉዞቻ
፲፫ ቸውንም ፡ ትቀድዳለህ ፡ አለው ። አዛሄልም ፡—
ይህን ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ እኔ ፡
ውሻ ፡ ባሪያህ ፡ ምንድር ፡ ነኝ ? አለ ። ኤልሳ
ዕም ፡— አንተ ፡ በሶርያ ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ እንድ
ትሆን ፡ እግዚአብሔር ፡ አሳይቶኛል ፡ አለው ።
፲፬ ከኤልሳዕም ፡ ርቆ ፡ ወደ ፡ ጌታው ፡ መጣ ፤ እር
ሱም ፡— ኤልሳዕ ፡ ምን ፡ አለህ ? አለው ። እር
፲፭ ሱም ፡— እንድትፈወስ ፡ ነገረኝ ፡ አለው ። በነ
ጋውም ፡ ለሐፍ ፡ ወስዶ ፡ በውኃ ፡ ነከረው ፡ በፊ
ቱም ፡ ላይ ፡ ሸፈነው ÷ ሞተም ። አዛሄልም ፡
በፋንታው ፡ ነገሠ ።

፲፮ በእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ በአክዓብ ፡ ልጅ ፡
በኢዮራም ፡ በአምስተኛው ፡ ዓመት ፡ የይሁዳ ፡
ንጉሥ ፡ የኢዮሣፍጥ ፡ ልጅ ፡ ኢዮራም ፡ ነገሠ ።
፲፯ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሠላሳ ፡ ሁለት ፡
ዓመት ፡ ጐልማሳ ፡ ነበረ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡
፲፰ ስምንት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። የአክዓብንም ፡ ልጅ ፡
አግብቶ ፡ ነበርና ፡ የአክዓብ ፡ ቤት ፡ እንዳደረገ ፡
በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ መንገድ ፡ ሄደ ፤ በእ
፲፱ ግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ። ነገር ፡
ግን ፡ ለእርሱና ፡ ለልጆቹ ፡ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡
መብራት ፡ ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ እንደ ፡
ሰጠ ÷ ስለ ፡ ባሪያው ፡ ስለ ፡ ዳዊት ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ይሁዳን ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ አልወደደም ።

፳ በእርሱም ፡ ዘመን ፡ ኤዶምያስ ፡ ለይሁዳ ፡
እንዳይገብር ፡ ሸፈተ ÷ በላያቸውም ፡ ንጉሥ ፡
፳፩ አነገሡ ። ኢዮራምም ፡ ከሰረገሎቹ ፡ ሁሉ ፡
ጋር ፡ ወደ ፡ ጸዒር ፡ አለፈ ፤ በሌሊትም ፡ ተነ
ሥቶ ፡ እርሱንና ፡ የሰረገሎቹን ፡ አለቆች ፡ ከብ
በው ፡ የነበሩትን ፡ የኤዶምያስን ፡ ሰዎች ፡ መታ ፤
፳፪ ሕዝቡ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ድንኳኑ ፡ ሸሸ ። ኤዶም
ያስ ፡ ግን ፡ ለይሁዳ ፡ እንዳይገብር ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡
ድረስ ፡ ሸፈተ ። በዚያም ፡ ዘመን ፡ ደግሞ ፡
፳፫ ልብና ፡ ሸፈተ ። የተረፈውም ፡ የኢዮራም ፡
ነገር ÷ ያደረገውም ፡ ሁሉ ÷ በይሁዳ ፡ ነገሥ
ታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለ
፳፬ ምን ? ኢዮራምም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀ
ላፋ ÷ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡
ተቀበረ ፤ በፋንታውም ፡ ልጁ ፡ አካዝያስ ፡ ነገሠ ።

፳፭ በእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ በአክዓብ ፡ ልጅ ፡
በኢዮራም ፡ በአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ዓመት ፡
የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ የኢዮራም ፡ ልጅ ፡ አካዝያስ ፡
፳፮ ነገሠ ። መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ አካዝያስ ፡
የሀያ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ጐልማሳ ፡ ነበረ ፤ በኢ
የሩሳሌምም ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። እናቱም ፡
ጎቶልያ ፡ የተባለች ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ የዘ
፳፯ ንበሪ ፡ ልጅ ፡ ነበረች ። በአክዓብም ፡ ቤት ፡ መን
ገድ ፡ ሄደ ÷ እንደ ፡ አክዓብም ፡ ቤት ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ፤ ለአክዓብ ፡ ቤት ፡
፳፰ አማች ፡ ነበረና ። ከአክዓብም ፡ ልጅ ፡ ከኢዮ
ራም ፡ ጋር ፡ የሶርያን ፡ ንጉሥ ፡ አዛሄልን ፡ በሬ
ማት ፡ ዘገለዓድ ፡ ሊጋጠም ፡ ሄደ ፤ ሶርያው
፳፱ ንም ፡ ኢዮራምን ፡ አቈሰሉት ። ንጉሡም ፡
ኢዮራም ፡ ከሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ ከአዛሄል ፡ ጋር ፡
በተዋጋ ፡ ጊዜ ፡ ሶርያውያን ፡ በሬማት ፡ ያቈሰ
ሉትን ፡ ቍስል ፡ ይታከም ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኢይ
ዝራኤል ፡ ተመለሰ ። የአክዓብም ፡ ልጅ ፡ ኢዮ
ራም ፡ ታምሞ ፡ ነበርና ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ የኢ
ዮራም ፡ ልጅ ፡ አካዝያስ ፡ ሊያየው ፡ ወደ ፡ ኢይ
ዝራኤል ፡ ወረደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ነቢዩም ፡ ኤልሳዕ ፡ ከነቢያት ፡ ልጆች ፡ አን
ዱን ፡ ጠርቶ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— ወገብህን ፡ ታጥ
ቀህ ፡ ይህን ፡ የዘይት ፡ ማሰሮ ፡ በእጅህ ፡ ያዝ ÷
፪ ወደ ፡ ሬማት ፡ ዘገለዓድም ፡ ሂድ ። በዚያም ፡
በደረስህ ፡ ጊዜ ፡ የናሜሲን ፡ ልጅ ፡ የኢዮሣፍ
ጥን ፡ ልጅ ፡ ኢዩን ፡ ታገኘዋለህ ፤ ገብተህም ፡
ከወንድሞቹ ፡ መካከል ፡ አስነሣው ÷ ወደ ፡
፫ ጓዳም ፡ አግባው ። የዘይቱንም ፡ ማሰሮ ፡ ይዘህ ፡
በራሱ ፡ ላይ ፡ አፍስሰውና ፡— እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡
ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ቀብሁህ ፡ በለው ፤ በሩንም ፡ ከፍ
፬ ተህ ፡ ሽሽ ÷ አትዘግይም ። እንዲሁም ፡ ጐልማ
ሳው ፡ ነቢይ ፡ ወደ ፡ ሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡ ሄደ ።
፭ በገባም ፡ ጊዜ ÷ እነሆ ÷ የሠራዊት ፡ አለቆች ፡
ተቀምጠው ፡ ነበር ፤ እርሱም ፡— አለቃ ፡ ሆይ ÷
ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነገር ፡ አለኝ ፡ አለ ። ኢዩም ፡—
ከማንኛችን ፡ ጋር ፡ ነው ? አለ ። እርሱም ፡—
፮ አለቃ ፡ ሆይ ÷ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነው ፡ አለ ። ተነ
ሥቶም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ገባ ፤ ዘይቱንም ፡ በራሱ ፡
ላይ ፡ አፍስሶ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— የእስራኤል ፡
አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
በእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡
፯ ንጉሥ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ቀብሁህ ። የባሪያዎቼን ፡
የነቢያትን ፡ ደም ÷ የእግዚአብሔርንም ፡ ባሪያ
ዎች ፡ ሁሉ ፡ ደም ፡ ከኤልዛቤል ፡ እጅ ፡ እበቀል ፡
ዘንድ ፡ የጌታህን ፡ የአክዓብን ፡ ቤት ፡ ትመታ
፰ ለህ ። የአክዓብም ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋል ፤ በእ
ስራኤልም ፡ ዘንድ ፡ የታሰረውንና ፡ የተለቀቀ
ውን ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ ከአክዓብ ፡ አጠፋለሁ ።
፱ የአክዓብንም ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ናባጥ ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡
ኢዮርብዓም ፡ ቤት ÷ እንደ ፡ አኪያም ፡ ልጅ ፡
፲ እንደ ፡ ባኦስ ፡ ቤት ፡ አደርገዋለሁ ። ኤልዛቤል
ንም ፡ በኢይዝራኤል ፡ እርሻ ፡ ውሾች ፡ ይበሉ
አታል ÷ የሚቀብራትም ፡ አታገኝም ። በሩንም ፡
ከፍቶ ፡ ሸሸ ።

፲፩ ኢዩም ፡ ወደ ፡ ጌታው ፡ ባሪያዎች ፡ ወጣ ፤ እነ
ርሱም ፡— ደኅና ፡ ነውን ? ይህ ፡ እብድ ፡ ለምን ፡
መጣብህ ? አሉት ። እርሱም ፡— ሰውዮውንና ፡
፲፪ ነገሩን ፡ ታውቃላችሁ ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡—
ሐሰት ፡ ነው ፤ ንገረን ፡ አሉት ፤ እርሱም ፡— እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በእስራኤል ፡
ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ቀብሁህ ፡ ብሎ ፡
፲፫ እንዲህ ፡ እንዲህ ፡ ነገረኝ ፡ አላቸው ። ሁሉም ፡
ፈጥነው ፡ ልብሳቸውን ፡ ወሰዱ ÷ በሰገነቱ ፡ መሰ
ላል ፡ እርከን ፡ ላይ ፡ ከእግሩ ፡ በታች ፡ አነጠ

ፉት ፥ ቀንደ ፡ መለከትም ፡ እየነፉ ፡— ኢዩ ፡ ነግ
ሦአል ፡ አሉ ።

፲፬፤ እንዲሁም ፡ የናሚሲ ፡ ልጅ ፡ የኢዮሣፍጥ ፡
ልጅ ፡ ኢዩ ፡ በኢዮራም ፡ ላይ ፡ ተማማለ ። ኢዮ
ራምና ፡ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ከሶርያ ፡
ንጉሥ ፡ ከአዛሄል ፡ የተነሣ ፡ ሬማት ፡ ዘገለዓድን ፡
፲፭፤ ይጠብቁ ፡ ነበር ። ንጉሡ ፡ ኢዮራም ፡ ግን ፡ ከሶ
ርያ ፡ ንጉሥ ፡ ከአዛሄል ፡ ጋር ፡ በተዋጋ ፡ ጊዜ ፡
ሶርያውያን ፡ ያቈሰሉትን ፡ ቍስል ፡ ይታከም ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኢይዝራኤል ፡ ተመልሶ ፡ ነበር ።
ኢዩም ፡— ልባችሁስ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ከሆነ ፡
በኢይዝራኤል ፡ እንዳያወራ ፡ ማንም ፡ ከከተማ ፡
፲፮፤ ኰብልሎ ፡ አይውጣ ፡ አለ ። ኢዮራምም ፡ በዚያ ፡
ታምሞ ፡ ተኝቶ ፡ ነበርና ፡ ኢዩ ፡ በሰረገላው ፡
ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ወደ ፡ ኢይዝራኤል ፡ ሄደ ። የይ
ሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ አካዝያስ ፡ ኢዮራምን ፡ ለማ
የት ፡ ወርዶ ፡ ነበር ።

፲፯፤ በኢይዝራኤልም ፡ ግንብ ፡ ላይ ፡ የቆመው ፡
ሰላይ ፡ የኢዩ ፡ ጭፍራ ፡ ሲመጣ ፡ አይቶ ፡—
ጭፍራ ፡ አያለሁ ፡ አለ ። ኢዮራምም ፡— የሚ
ገናኘው ፡ ፈረሰኛ ፡ ላክ ፥ እርሱም ፡— ሰላም ፡
፲፰፤ ነውን ? ይበለው ፡ አለ ። ፈረሰኛውም ፡ ሊገና
ኘው ፡ ሄዶ ፡— ንጉሡ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ሰላም ፡ ነውን ? አለ ። ኢዩም ፡— አንተ ፡ ከሰ
ላም ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አለህ ? ወደ ፡ ኋላዬ ፡ አልፈህ ፡
ተከተለኝ ፡ አለ ። ሰላዩም ፡— መልእክተኛው ፡
ደረሰባቸው ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አልተመለሰም ፡ ብሎ ፡
፲፱፤ ነገረው ። ሁለተኛም ፡ ፈረሰኛ ፡ ሰደደ ፥ ወደ ፡
እነርሱም ፡ ደርሶ ፡— ንጉሡ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ሰላም ፡ ነውን ? አለ ። ኢዩም ፡— አንተ ፡ ከሰ
ላም ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አለህ ? ወደ ፡ ኋላዬ ፡ አልፈህ ፡
፳፤ ተከተለኝ ፡ አለ ። ሰላዩም ፡— ደረሰባቸው ፥
ነገር ፡ ግን ፡ አልተመለሰም ፤ በችኰላ ፡ ይሄዳልና ፡
አካሄዱ ፡ እንደ ፡ ናሚሲ ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ኢዩ ፡
አካሄድ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ነገረው ።

፳፩፤ ኢዮራምም ፡— ሰረገላ ፡ አዘጋጁ ፡ አለ ፤ ሰረገ
ላውንም ፡ አዘጋጁለት ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡
ኢዮራም ፡ የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ አካዝያስ ፡ በሰ
ረገሎቻቸው ፡ ተቀምጠው ፡ ወጡ ፥ ኢዩንም ፡
ሊገናኙት ፡ ሄዱ ፤ በኢይዝራኤላዊው ፡ በና
፳፪፤ ቡቴ ፡ እርሻ ፡ ውስጥ ፡ አገኙት ። ኢዮራምም ፡
ኢዩን ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡— ኢዩ ፡ ሆይ ፥ ሰላም ፡ ነውን ?
አለ ። እርሱም ፡— የእናትህ ፡ የኤልዛቤል ፡ ግል
ሙትናዋና ፡ መተትዋ ፡ ሲበዛ ፡ ምን ፡ ሰላም ፡
፳፫፤ አለ ? ብሎ ፡ መለሰ ። ኢዮራምም ፡ መልሶ ፡
ነዳና ፡ ሸሸ ፥ አካዝያስንም ፡— አካዝያስ ፡ ሆይ ፥
፳፬፤ ዓመፅ ፡ ነው ፡ አለው ። ኢዩም ፡ በእጁ ፡ ቀስ
ቱን ፡ ለጠጠ ፥ ኢዮራምንም ፡ በጫንቃው ፡ መካ
ከል ፡ወጋው ፤ ፍላጻውም ፡ በልቡ ፡ አለፈ ፥ ወደ ፡
፳፭፤ ሰረገላውም ፡ ውስጥ ፡ ወደቀ ። ኢዩም ፡ አለቃ
ውን ፡ ቢድቃርን ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— አንሥ
ተህ ፡ በኢይዝራኤላዊው ፡ በናቡቴ ፡ እርሻ ፡
ጣለው ፥ አንተና ፡ እኔ ፡ ጐን ፡ ለጐን ፡ በፈረስ ፡
ተቀምጠን ፡ አባቱን ፡ አክዓብን ፡ በተከተልን ፡
ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ይህን ፡
፳፮፤ መከራ ፡ እንደ ፡ ተናገረበት ፡ አስብ ፡— በእው
ነት ፡ የናቡቴንና ፡ የልጆቹን ፡ ደም ፡ ትናንትና ፡
አይቻለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፥ በዚህም ፡
እርሻ ፡ እመልስብሃለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡
ቃል ፡ ወስደህ ፡ በእርሻው ፡ ውስጥ ፡ ጣለው ።

፳፯፤ የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ አካዝያስ ፡ ያንን ፡ በየ ፡
ጊዜ ፡ በአትክልት ፡ ቤት ፡ መንገድ ፡ ሸሸ ።
ኢዩም ፡— ይህን ፡ ደግሞ ፡ በሰረገላው ፡ ላይ ፡
ውጉት ፡ እያለ ፡ ተከተለው ፤ በይብለዓምም ፡ አቅ
ራቢያ ፡ ባለችው ፡ በጉር ፡ ዐቀበት ፡ ላይ ፡ ወጉት ።
፳፰፤ ወደ ፡ መጊዶም ፡ ሸሸ ፥ በዚያም ፡ ሞተ ። ባሪያ
ዎቹም ፡ በሰረገላው ፡ ጭነው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳ
ሌም ፡ ወሰዱት ፥ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ በመቃ
ብሩ ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ቀበሩት ።

፳፱፤ በአክዓብም ፡ ልጅ ፡ በኢዮራም ፡ በአሥራ ፡
አንደኛው ፡ ዓመት ፡ አካዝያስ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡
ነገሠ ።

፴፤ ኢዩም ፡ ወደ ፡ ኢይዝራኤል ፡ መጣ ፤ ኤልዛ
ቤልም ፡ በሰማች ፡ ጊዜ ፡ ዓይንዋን ፡ ተኳለች ፥
ራስዋንም ፡ አስጌጠች ፥ በመስኮትም ፡ ዘልቃ ፡
፴፩፤ ትመለከት ፡ ነበር ። ኢዩም ፡ በበሩ ፡ ሲገባ ፡—
ጌታውን ፡ የገደለ ፡ ዘምሪ ፡ ሆይ ፥ ሰላም ፡ ነውን ?
፴፪፤ አለችው ። ፊቱንም ፡ ወደ ፡ መስኮቱ ፡ አን
ሥቶ ፡— ከእኔ ፡ ጋር ፡ ማን ፡ ነው ? አለ ። ሁለት ፡
ሦስትም ፡ ጃንደረቦች ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተመለከቱ ።
፴፫፤ እርሱም ፡— ወደ ፡ታች ፡ ወርውሩአት ፡ አለ ፤
ወረወሩአትም ፥ ደምዋም ፡ በግንቡና ፡ በፈረ
፴፬፤ ሶቹ ፡ ላይ ፡ ተረጨ ፥ ረገጡአትም ። በገባም ፡
ጊዜ ፡ በላ ፡ ጠጣም ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡— ይህ
ችን ፡ የተረገመች ፡ እዩ ፤ የንጉሥ ፡ ልጅ ፡ ናትና ፡
፴፭፤ ቅበሩአት ፡ አለ ። ሊቀብሩአትም ፡ በሄዱ ፡ ጊዜ ፡
ከአናትዋና ፡ ከእግርዋ ፡ ከመዳፍም ፡ በቀር ፡
፴፮፤፴፯፤ ምንም ፡ አላገኙም ። ተመልሰውም ፡ ነገሩት ፤
እርሱም ፡— በባሪያው ፡ በቴስብያዊ ፡ ኤልያስ ፡—
በኢይዝራኤል ፡ እርሻ ፡ የኤልዛቤልን ፡ ሥጋ ፡
ውሾች ፡ ይበላሉ ፤ የኤልዛቤልም ፡ ሬሳ ፡ በኢ
ይዝራኤል ፡ እርሻ ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ፍግ ፡
ይሆናልና ፡ ማንም ፡— ይህች ፡ ኤልዛቤል ፡ ናት ፡
ይል ፡ ዘንድ ፡ አይችልም ፡ ብሎ ፡ የተናገረው ፡
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፤ ለአክዓብም ፡ በሰማርያ ፡ ሰባ ፡ ልጆች ፡ ነበ
ሩት ፤ ኢዩም ፡ ደብዳቤ ፡ ጻፈ ፤ የአክዓብን ፡
ልጆች ፡ ለሚያሳድጉ ፡ ለሰማርያ ፡ ታላላቆችና ፡
፪፤ ሽማግሌዎች ፡— ይህ ፡ ደብዳቤ ፡ አሁን ፡ በደረሰ
ችሁ ፡ ጊዜ ፡ የጌታችሁ ፡ ልጆች ፡ ሰረገሎችና ፡
ፈረሶችም ፡ የተመሸገችም ፡ ከተማ ፡ መሣሪያዎ
፫፤ ችም ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ አሉና ፥ ከጌታችሁ ፡
ልጆች ፡ ደስ ፡ የሚያሰኛችሁንና ፡ የሚሻላች
ሁን ፡ ምረጡ ፥ በአባቱም ፡ ዙፋን ፡ አስቀም
ጡት ፥ ስለ ፡ ጌታችሁም ፡ ቤት ፡ ተዋጉ ፡ ብሎ ፡

፬ ወደ ፡ ሰማርያ ፡ ሰደደ ። እነርሱ ፡ ግን ፡ እጅግ ፡
ፈርተው ፡— እነሆ ÷ ሁለቱ ፡ ነገሥታት ፡ በፊቱ ፡
ይቆሙ ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉም ፤ እኛስ ፡ እንዴት ፡
፭ እንቆማለን ? አሉ ። የቤቱ ፡ አለቃ ÷ የከተማይ
ቱም ፡ አለቃ ÷ ሽማግሌዎችና ፡ ልጆቹን ፡ የሚ
ያሳድጉ ፡— እኛ ፡ ባሪያዎችህ ፡ ነን ÷ ያዘዝኸን
ንም ፡ ሁሉ ፡ እናደርጋለን ፤ ንጉሥም ፡ በላያ
ችን ፡ አናነግሥም ፤ የምትወድደውን ፡ አድ
፮ ርግ ፡ ብለው ፡ ወደ ፡ ኢዩ ፡ ላኩ ። ሁለተኛም ፡—
ወገኖቼስ ፡ እንደ ፡ ሆናችሁ ÷ ነገሬንም ፡ ከሰማ
ችሁ ÷ የጌታችሁን ፡ ልጆች ፡ ራስ ፡ ቍረጡ ÷
ነገም ፡ በዚህ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ኢይዝራኤል ፡
ወደ ፡ እኔ ፡ ይዛችሁ ፡ ኑ ፡ ብሎ ፡ ደብዳቤ ፡ ጻፈ
ላቸው ። የንጉሡም ፡ ልጆች ፡ ሰባው ፡ ሰዎች ፡
በሚያሳድጓቸው ፡ በከተማይቱ ፡ ታላላቆች ፡
፯ ዘንድ ፡ ነበሩ ። ደብዳቤውም ፡ በደረሳቸው ፡
ጊዜ ፡ የንጉሡን ፡ ልጆች ፡ ሰባውን ፡ ሰዎች ፡
ይዘው ፡ ገደሉአቸው ፤ ራሳቸውንም ፡ በቅር
ጫት ፡ አድርገው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ወደ ፡ ኢይዝ
፰ ራኤል ፡ ላኩ ። መልእክተኛም ፡ መጥቶ ፡— የን
ጉሡን ፡ ልጆች ፡ ራስ ፡ ይዘው ፡ መጥተዋል ፡
ብሎ ፡ ነገረው ። እርሱም ፡— እስከ ፡ ነገ ፡ ድረስ ፡
በበሩ ፡ አደባባይ ፡ ሁለት ፡ ክምር ፡ አድርጋ
፱ ችሁ ፡ አኑሩአቸው ፡ አለ ። በነጋውም ፡ ወጥቶ ፡
ቆመ ÷ ሕዝቡንም ፡ ሁሉ ፡— እናንተ ፡ ንጹሐን ፡
ናችሁ ፤ እነሆ ÷ ጌታዬን ፡ የወነጀልሁ ፡ የገደል
ሁትም ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ እነዚህንስ ፡ ሁሉ ፡ የገደለ ፡
፲ ማን ፡ ነው ? እግዚአብሔር ፡ በአክዓብ ፡ ቤት ፡
ላይ ፡ ከተናገረው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በም
ድር ፡ ላይ ፡ አንዳች ፡ እንዳይወድቅ ፡ አሁን ፡
እወቁ ፤ እግዚአብሔር ፡ በባሪያው ፡ በኤልያስ ፡
፲፩ የተናገረውን ፡ አድርጎአል ፡ አላቸው ። ኢዩም ፡
ከአክዓብ ፡ ቤት ፡ የቀረውን ፡ ሁሉ ÷ ታላላቆቹ
ንም ፡ ሁሉ ÷ ወዳጆቹንና ፡ ካህናቱን ፡ ማንም ፡
ሳይቀር ፡ በኢይዝራኤል ፡ ገደላቸው ።
፲፪ ተነሥቶም ፡ ወደ ፡ ሰማርያ ፡ ሄደ ፤ በመንገ
ድም ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ በግ ፡ ጠባቂዎች ፡ ቤት ፡
፲፫ በደረሰ ፡ ጊዜ ÷ ኢዩ ፡ ከይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ከአካዝ
ያስ ፡ ወንድሞች ፡ ጋር ፡ ተገናኝቶ ፡— እናንተ ፡
እነማን ፡ ናችሁ ? አለ ። እነርሱም ፡— እኛ ፡ የአ
ካዝያስ ፡ ወንድሞች ፡ ነን ፤ የንጉሡንና ፡ የእቴ
ጌይቱን ፡ ልጆች ፡ ደኅንነት ፡ ለመጠየቅ ፡ እንወ
፲፬ ርዳለን ፡ አሉት ። እርሱም ፡— በሕይወታቸው ፡
ያዙአቸው ፡ አለ ። ያዙአቸውም ÷ በበግ ፡ ጠባ
ቂዎችም ፡ ቤት ፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡ ጕድጓድ ፡
አርባ ፡ ሁለቱን ፡ ሰዎች ፡ ገደሉአቸው ፤ ማን
ንም ፡ አላስቀረም ።
፲፭ ከዚያም ፡ በሄደ ፡ ጊዜ ፡ የሬካብን ፡ ልጅ ፡ ኢዮ
ናዳብን ፡ ተገናኘው ፤ ደኅንነቱንም ፡ ጠይቆ ፡—
ልቤ ፡ ከልብህ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያህል ፡
ልብህ ፡ ከልቤ ፡ ጋር ፡ በቅንነት ፡ ነውን ? አለው ፤
ኢዮናዳብም ፡— እንዲሁ ፡ ነው ፡ አለው ።
ኢዩም ፡— እንዲሁ ፡ እንደ ፡ ሆነስ ፡ እጅህን ፡
ስጠኝ ፡ አለ ። እጁንም ፡ ሰጠው ፤ ወደ ፡ ሰረገላ

ውም ፡ አውጥቶ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አስቀመጠ
፲፮ ውና ፡— ከእኔ ፡ ጋር ፡ ና ÷ ለእግዚአብሔርም ፡
መቅናቴን ፡ እይ ፡ አለው ። በሰረገላውም ፡ አስ
፲፯ ቀመጠው ። ወደ ፡ ሰማርያም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡
ለኤልያስ ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ እንደ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ቃል ፡ እስኪያጠፋው ፡ ድረስ ፡ ከአክ
ዓብ ፡ በሰማርያ ፡ የቀረውን ፡ ሁሉ ፡ ገደለ ።
፲፰ ኢዩም ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ሰብስቦ ፡— አክዓብ ፡
በአልን ፡ በጥቂቱ ፡ አመለከው ፤ ኢዩ ፡ ግን ፡
፲፱ በብዙ ፡ ያመልከዋል ። አሁንም ፡ የበአልን ፡
ነቢያት ፡ ሁሉ ÷ አገልጋዮቹንም ፡ ሁሉ ÷ ካህና
ቱንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ጥሩ ፤ ማንም ፡ አይ
ቅር ፤ ለበአል ፡ ታላቅ ፡ መሥዋዕት ፡ አቀርባ
ለሁ ÷ የቀረውም ፡ ሁሉ ፡ በሕይወት ፡ አይኖ
ርም ፡ አላቸው ። ኢዩም ፡ የበአልን ፡ አገልጋ
ጋዮች ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ በተንኰል ፡ ይህን ፡
፳ አደረገ ። ኢዩም ፡— ለበአል ፡ ዋና ፡ ጉባኤ ፡
፳፩ ቀድሱ ፡ አለ ። እነርሱም ፡ አወጁ ። ኢዩም ፡
ወደ ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ላከ ÷ የበአልም ፡ አገ
ልጋዮች ፡ ሁሉ ፡ መጡ ፤ ሳይመጣ ፡ የቀረ ፡
አንድ ፡ ስንኳ ፡ አልነበረም ። ወደ ፡ በአልም ፡
ቤት ፡ ገቡ ÷ የበአልም ፡ ቤት ፡ ከዳር ፡ እስከ ፡
፳፪ ዳር ፡ ድረስ ፡ ሞልቶ ፡ ነበር ። ዕቃ ፡ ቤቱንም ፡—
ለበአል ፡ አገልጋዮች ፡ ሁሉ ፡ ልብስ ፡ አውጣ ፡
፳፫ አለው ። ልብሱንም ፡ አወጣላቸው ። ኢዩም ፡
የሬካብም ፡ ልጅ ፡ ኢዮናዳብ ፡ ወደ ፡ በአል ፡
ቤት ፡ ገቡ ። የበአልንም ፡ አገልጋዮች ፡— መር
ምሩ ÷ ከበአል ፡ አገልጋዮች ፡ ብቻ ፡ በቀር ፡
እግዚአብሔርን ፡ ከሚያመልኩ ፡ ወገን ፡ በእና
ንተ ፡ ዘንድ ፡ አንድ ፡ እንኳ ፡ እንዳይኖር ፡ ተመ
፳፬ ልከቱ ፡ አላቸው ። የሚቃጠል ፡ መሥዋዕትና ፡
ሌላ ፡ መሥዋዕትም ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡ ገቡ ፤
ኢዩም ፡— በእጃችሁ ፡ አሳልፌ ፡ ከምሰጣችሁ ፡
ሰዎች ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ያመለጠ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ነፍሱ ፡ በዚያ ፡ ነፍስ ፡ ፋንታ ፡ ትሆናለች ፡ ብሎ ፡
በውጪ ፡ ሰማንያ ፡ ሰዎችን ፡ አዘጋጅቶ ፡ ነበር ።
፳፭ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ አቅርበው ፡
በፈጸሙ ፡ ጊዜ ፡ ኢዩ ፡ ዘበኞቹንና ፡ አለቆቹን ፡—
ግቡና ፡ ግደሉአቸው ፤ አንድም ፡ አይውጣ ፡
አላቸው ። በሰይፍም ፡ ስለት ፡ ገደሉአቸው ፤
ዘበኞችና ፡ አለቆችም ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ጣሉአ
ቸው ÷ ወደ ፡ በአልም ፡ ቤት ፡ ከተማ ፡ ሄዱ ።
፳፮ ከበአልም ፡ ቤት ፡ ሐውልቶቹን ፡ አወጡ ፡ አቃ
፳፯ ጠሉአቸውም ። የበአልን ፡ ሐውልት ፡ ቀጠ
ቀጡ ÷ የበአልንም ፡ ቤት ፡ አፈረሱ ÷ እስከ ፡
ዛሬም ፡ ድረስ ፡ የውዳቂ ፡ መጣያ ፡ አደረጉት ።
፳፰ እንዲሁም ፡ ኢዩ ፡ በአልን ፡ ከእስራኤል ፡
፳፱ አጠፋ ። ነገር ፡ ግን ፡ እስራኤልን ፡ ካሳተው ፡
ከናባጥ ፡ ልጅ ፡ ከኢዮርብዓም ፡ ኃጢአት ÷
በቤቴልና ፡ በዳን ፡ ከነበሩት ፡ ከወርቁ ፡ እምቦ
፴ ሶች ÷ ኢዩ ፡ አልራቀም ። እግዚአብሔርም ፡
ኢዩን ፡— በፊቴ ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አድርገሃልና ÷
በልቤም ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ በአክዓብ ፡ ቤት ፡
ላይ ፡ አድርገሃልና ፡ ልጆችህ ፡ እስከ ፡ አራት ፡

ትውልድ ፡ ድረስ ፡ በእስራኤል ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡
፴፩ ይቀመጣሉ ፡ አለው ። ኢዩ ፡ ግን ፡ በእስራኤል ፡
አምላክ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ በፍጹም ፡
ልቡ ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ አልተጠነቀቀም ፤ እስራ
ኤልንም ፡ ካሳተው ፡ ከኢዮርብዓም ፡ ኀጢአት ፡
አልራቀም ።
፴፪ በዚያም ፡ ወራት ፡ እግዚአብሔር ፡ እስራኤ
ልን ፡ ይከፋፍላቸው ፡ ዘንድ ፡ ጀመረ ፤ አዛሄ
ልም ፡ በእስራኤል ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ መታቸው ።
፴፫ በዮርዳኖስ ፡ ምሥራቅ ፡ ያለውን ፡ የገለዓድን ፡
አገር ፡ ሁሉ ፥ በአርኖን ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ ካለ
ችው ፡ ከአሮዔር ፡ ጀምሮ ፡ የጋድንና ፡ የሮቤ
ልን ፡ የምናሴንም ፡ አገር ፥ ገለዓድንና ፡ ባሳንን ፡
፴፬ መታ ። የቀረውም ፡ የኢዩ ፡ ነገር ፥ የሠራውም ፡
ሥራ ፡ ሁሉ ፥ ጭከናውም ፡ ሁሉ ፥ በእስራ
ኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡
፴፭ አይደለምን ? ኢዩም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀ
ላፋ ፥ በሰማርያም ፡ ቀበሩት ። በፋንታውም ፡
፴፮ ልጁ ፡ ኢዮአካዝ ፡ ነገሠ ። ኢዩም ፡ በሰማርያ ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ የነገሠበት ፡ ዘመን ፡ ሀያ ፡
ስምንት ፡ ዓመት ፡ ነበረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ የአካዝያስም ፡ እናት ፡ ጎቶልያ ፡ ልጅዋ ፡
እንደ ፡ ሞተ ፡ በየች ፡ ጊዜ ፡ ተነሥታ ፡ የመንግ
፪ ሥትን ፡ ዘር ፡ ሁሉ ፡ አጠፋች ። የንጉሡ ፡ የኢ
ዮራም ፡ ልጅ ፡ የአካዝያስ ፡ እኅት ፡ ዮሳቤት ፡
የአካዝያስን ፡ ልጅ ፡ ኢዮአስን ፡ ወስዳ ፡ ከተገ
ደሉት ፡ ከንጉሥ ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ሰረቀ
ችው ፤ እርሱንና ፡ ሞግዚቱንም ፡ ወደ ፡ እል
ፍኝ ፡ ወሰደች ፥ እንዳይገደልም ፡ ከጎቶልያ ፡
፫ ሸሸጉት ። በእርስዋም ፡ ዘንድ ፡ ተሸሽጎ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡
ተቀመጠ ። ጎቶልያም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ነገሠች ።
፬ በሰባተኛውም ፡ ዓመት ፡ ዮዳሄ ፡ ልኮ ፡ በካራ
ውያንና ፡ በዘበኞች ፡ ላይ ፡ ያሉትን ፡ የመቶ ፡
አለቆች ፡ ወሰደ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡
ቤት ፡ አገባቸው ፤ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ቃል ፡
ኪዳን ፡ አደረገ ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡
አማላቸው ፥ የንጉሡንም ፡ ልጅ ፡ አሳያቸው ።
፭ እንዲህም ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ፡— እንዲህ ፡ አድ
ርጉ ፤ በሰንበት ፡ ቀን ፡ ከምትገቡት ፡ ከእናንተ ፡
ከሦስት ፡ አንዱ ፡ እጅ ፡ የንጉሡን ፡ ቤት ፡ ዘብ ፡
፮ ጠብቁ ፤ ከእናንተ ፡ ከሦስት ፡ አንዱ ፡ እጅ ፡
በሱር ፡ በር ፡ ሁኑ ፤ አንዱም ፡ እጅ ፡ ከዘበ
ኞች ፡ ቤት ፡ በኋላ ፡ ባለው ፡ በር ፡ ሁኑ ፤ ቤቱ
፯ ንም ፡ ጠብቁ ፥ ከልክሉም ፤ ከእናንተም ፡ በሰ
ንበት ፡ ቀን ፡ የምትወጡት ፡ ሁለቱ ፡ እጅ ፡
በንጉሥ ፡ ዙሪያ ፡ ሆናችሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡
፰ ቤት ፡ ጠብቁ ። ንጉሡንም ፡ በዙሪያው ፡ ክበ
ቡት ፥ የጦር ፡ ዕቃችሁም ፡ በእጃችሁ ፡ ይሁን ፤
በሰልፋችሁም ፡ መካከል ፡ የሚገባ ፡ ይገደል ፤ ንጉ
ሡም ፡ በወጣና ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሁኑ ።
፱ መቶ ፡ አለቆችም ፡ ካህኑ ፡ ዮዳሄ ፡ ያዘዘውን ፡
ሁሉ ፡ አደረጉ ፤ ከእነርሱም ፡ እያንዳንዱ ፡ በሰ
ንበት ፡ ይገቡ ፡ የነበሩትን ፥ በሰንበቱም ፡
ይወጡ ፡ የነበሩትን ፡ ሰዎች ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡
፲ ካህኑ ፡ ወደ ፡ ዮዳሄ ፡ መጡ ። ካህኑም ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የነበረውን ፡ የንጉሡን ፡ የዳ
ዊትን ፡ ጋሻና ፡ ጦር ፡ ሁሉ ፡ ለመቶ ፡ አለቆች ፡
፲፩ ሰጣቸው ። ዘበኞቹም ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዳቸው ፡
የጦር ፡ ዕቃቸውን ፡ በእጃቸው ፡ ይዘው ፡ በን
ጉሡ ፡ ዙሪያ ፡ ከቤቱ ፡ ቀኝ ፡ እስከ ፡ ቤቱ ፡ ግራ ፡
ድረስ ፡ በመሠዊያውና ፡ በቤቱ ፡ አጠገብ ፡ ቆሙ ።
፲፪ የንጉሡንም ፡ ልጅ ፡ አውጥቶ ፡ ዘውዱን ፡ ጫነ
በት ፥ ምስክሩንም ፡ ሰጠው ፤ ቀብተውም ፡
ንጉሥ ፡ አደረጉትና ፡— ንጉሡ ፡ ሺህ ፡ ዓመት ፡
ይንገሥ ፡ እያሉ ፡ እጃቸውን ፡ አጨበጨቡ ።
፲፫ ጎቶልያም ፡ የሠራዊቱንና ፡ የሕዝቡን ፡ ድምፅ ፡
በሰማች ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ ወደ ፡ እግዚአ
፲፬ ብሔር ፡ ቤት ፡ መጣች ። እነሆም ፥ ንጉሡ ፡
እንደ ፡ ተለመደው ፡ በዓምዱ ፡ አጠገብ ፡ ቆሞ ፥
ከንጉሡም ፡ ጋር ፡ አለቆችና ፡ መለከተኞች ፡
ቆመው ፡ አየች ፤ የአገሩም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡
ደስ ፡ ብሎአቸው ፡ ቀንደ ፡ መለከት ፡ ይነፉ ፡
ነበር ። ጎቶልያም ፡ ልብስዋን ፡ ቀድዳ ፡—
ዓመፅ ፡ ነው ፥ ዓመፅ ፡ ነው ፡ ብላ ፡ ጮኸች ።
፲፭ ካህኑም ፡ ዮዳሄ ፡ በጭፍራው ፡ ላይ ፡ የተሾሙ
ትን ፡ የመቶ ፡ አለቆች ፡— ወደ ፡ ሰልፉ ፡ መካ
ከል ፡ አውጡአት ፤ የሚከተላትንም ፡ በሰይፍ ፡
ግደሉት ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ፤ ካህኑ ፡— በእግ
ዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አትገደል ፡ ብሎአልና ።
፲፮ እጃቸውንም ፡ በእርስዋ ፡ ላይ ፡ ጫኑ ፥ በፈረሱም ፡
መግቢያ ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡ ቤት ፡ ወሰ
ዱአት ፥ በዚያም ፡ ገደሉአት ።
፲፯ ዮዳሄም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡ ይሆኑ ፡
ዘንድ ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በንጉሡ ፡ በሕዝ
ቡም ፡ መካከል ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረገ ፤ ደግ
ሞም ፡ በንጉሡና ፡ በሕዝቡ ፡ መካከል ፡ ቃል ፡
፲፰ ኪዳን ፡ አደረገ ። የአገሩም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ በኣል ፡ ቤት ፡ ሄደው ፡ አፈረሱት ፤ መሠ
ዊያዎቹንና ፡ ምስሎቹን ፡ አደቀቁ ፥ የበኣልንም ፡
ካህን ፡ ማታንን ፡ በመሠዊያው ፡ ፊት ፡ ገደሉት ።
ካህኑም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አስተዳዳሪዎ
፲፱ ችን ፡ ሾመ ። መቶ ፡ አለቆቹንና ፡ ካራውያንንም ፥
ዘበኞችንና ፡ የአገሩንም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ወሰደ ፤
ንጉሡንም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አወረዱት ፥
በዘበኞችም ፡ በር ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡
ቤት ፡ አመጡት ፤ በነገሥታቱም ፡ ዙፋን ፡ ተቀ
፳ መጠ ። የአገሩም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ አላ
ቸው ፥ ከተማይቱም ፡ ጸጥ ፡ አለች ። ጎቶልያንም ፡
በንጉሡ ፡ ቤት ፡ አጠገብ ፡ በሰይፍ ፡ ገደሉአት ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ ኢዮአስም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሰ
፪ ባት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ። በኢዩ ፡ በሰባተኛው ፡
ዓመት ፡ ኢዮአስ ፡ መንገሥ ፡ ጀመረ ፥ በኢየ
ሩሳሌምም ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡

ሳብያ ፡ የተባለች ፡ የቤርሳቤህ ፡ ሴት ፡ ነበረች ።
፪ ካህኑ ፡ ዮዳሄም ፡ ያስተምረው ፡ በነበረ ፡ ዘመን ፡
ሁሉ ፡ ኢዮአስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቅን ፡
፫ ነገር ፡ አደረገ ። ነገር ፡ ግን ፡ በኮረብቶቹ ፡ ላይ ፡
ያሉት ፡ መስገጃዎች ፡ አልተወገዱም ፤ ሕዝቡም ፡
ገና ፡ በኮረብቶቹ ፡ ላይ ፡ ባሉት ፡ መስገጃዎች ፡
ይሠዋና ፡ ያጥን ፡ ነበር ።
፬ ኢዮአስም ፡ ካህናቱን ፡— ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ቤት ፡ የሚገባውን ፡ የተቀደሰውን ፡ ገን
ዘብ ፡ ሁሉ ÷ ስለ ፡ ነፍሱም ፡ ዋጋ ፡ የሚቀርበ
ውን ፡ ገንዘብ ÷ በልባቸውም ፡ ፈቃድ ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የሚያመጡትን ፡ ገንዘብ ፡
፭ ሁሉ ÷ ካህናቱ ፡ እያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ ከሚያ
መጣው ፡ ይውሰዱ ፡ በመቅደስም ፡ ውስጥ ፡
፮ የተናዱትን ፡ ይጠግኑበት ፡ አላቸው ። ነገር ፡
ግን ፡ እስከ ፡ ንጉሡ ፡ እስከ ፡ ኢዮአስ ፡ እስከ ፡
ሀያ ፡ ሦስተኛው ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ በመቅደሱ ፡
ውስጥ ፡ የተናዱትን ፡ ካህናቱ ፡ አልጠገኑትም ፡
፯ ነበር ። ኢዮአስም ፡ ካህኑን ፡ ዮዳሄንና ፡ ካህና
ቱን ፡ ጠርቶ ፡— በመቅደሱ ፡ ውስጥ ፡ የተናዱ
ትን ፡ ስፍራዎች ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አትጠግኑአቸ
ውም ? ከእንግዲህ ፡ ወዲያ ፡ ገንዘቡ ፡ ለቤቱ ፡
መጠገኛ ፡ ይሰጥ ፡ እንጂ ፡ ከሚያመጡት ፡ ሰዎች ፡
፰ አትቀበሉ ፡ አላቸው ። ካህናቱም ፡— ከሕዝቡ ፡
ገንዘቡን ፡ እንወስድም ÷ በቤቱም ፡ ውስጥ ፡ የተ
ናዱትን ፡ እንጠግንም ፡ ብለው ፡ እሺ ፡ አሉ ።
፱ ካህኑ ፡ ዮዳሄ ፡ ግን ፡ ሣጥን ፡ ወስዶ ፡ መክደ
ኛውን ፡ ነደለው ÷ በመሠዊያውም ፡ አጠገብ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በሚገቡበት ፡ መግ
ቢያ ፡ በስተ ፡ ቀኝ ፡ አኖረው ፤ ደጁንም ፡ የሚጠ
ብቁ ፡ ካህናት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የሚ
መጣውን ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉ ፡ ያኖሩበት ፡ ነበር ።
፲ በሣጥንም ፡ ውስጥ ፡ ብዙ ፡ ገንዘብ ፡ መኖሩን ፡
በዩ ፡ ጊዜ ፡ የንጉሡ ፡ ጸሐፊና ፡ የካህናቱ ፡ አለቃ ፡
ይመጡ ፡ ነበር ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ የተ
ገኘውን ፡ ቈጥረው ፡ በከረጢት ፡ ውስጥ ፡ ያኖ
፲፩ ሩት ፡ ነበር ። የተመዘነውንም ፡ ገንዘብ ፡ የእግ
ዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ለመሥራት ፡ በተሾሙት ፡
፲፪ እጅ ፡ ይሰጡ ፡ ነበር ። የተናደውን ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ቤት ፡ ለመጠገን ፡ መክፈል ፡ ለሚያ
ሻው ፡ ሁሉ ፡ ድንጋይና ፡ እንጨት ፡ ይገዙ ፡
ዘንድ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ለሚሠሩ ፡
አናጢዎችና ፡ ሠራተኞች ፡ ግንበኞችና ፡ ድን
፲፫ ጋይ ፡ ወቃሪዎች ፡ ይሰጡት ፡ ነበር ። ነገር ፡
ግን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ከሚመጣው ፡
ገንዘብ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የሚሆኑ ፡
የብር ፡ ጽዋዎችና ፡ ጕጠቶች ፡ ድስቶችም ፡ መለ
ከቶችም ፡ የወርቅና ፡ የብር ፡ ዕቃዎችም ፡ አል
፲፬ ተሠሩም ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ ለሚሠሩት ፡ ይሰ
ጡት ፡ ነበር ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ ጠገ
፲፭ ኑበት ። ለሠራተኞችም ፡ ይከፍሉ ፡ ዘንድ ፡
ገንዘቡን ፡ የሚወስዱትን ፡ ሰዎች ፡ አይቈጣጠሩ
አቸውም ፡ ነበር ፤ በታማኝነት ፡ ይሠሩ ፡ ነበርና ።
፲፮ ስለ ፡ በደልና ፡ ስለ ፡ ኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡
የቀረበውም ፡ ገንዘብ ፡ ለካህናት ፡ ነበረ ፡ እንጂ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አያገቡትም ፡ ነበር ።
፲፯ በዚያም ፡ ወራት ፡ የሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ አዛሄል ፡
ወጥቶ ፡ ጌትን ፡ ወጋ ÷ ያዘውም ፤ አዛሄልም ፡
ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ለመውጣት ፡ ፊቱን ፡ አቀና ።
፲፰ የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮአስ ፡ አባቶቹ ፡ የይ
ሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ኢዮሣፍጥና ፡ ኢዮራም ፡ አካ
ዝያስም ፡ የቀደሱትን ፡ ቅዱስ ፡ ነገር ÷ እርሱም ፡
የቀደሰውን ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ቤትና ፡ በን
ጉሡ ፡ ቤት ፡ መዛግብት ፡ የተገኘውን ፡ ወርቅ ፡
ሁሉ ፡ ወሰደ ÷ ወደ ፡ ሶርያም ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ አዛ
ሄል ፡ ላከው ። እርሱም ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ተመ
ለሰ ።
፲፱ የቀረውም ፡ የኢዮአስ ፡ ነገር ÷ የሠራውም ፡
ሥራ ፡ ሁሉ ÷ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽ
፳ ሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ባሪያዎቹም ፡ ተነ
ሥተው ፡ ዐመፁበት ÷ ወደ ፡ ሲላ ፡ በሚወርደ
፳፩ ውም ፡ መንገድ ፡ በሚሎ ፡ ቤት ፡ ገደሉት ። ባሪ
ያዎቹም ፡ የሰምዓት ፡ ልጅ ፡ ዮዛካርና ፡ የሾሜር ፡
ልጅ ፡ ዮዛባት ፡ መቱት ÷ ሞተም ፤ በዳዊትም ፡
ከተማ ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ቀበሩት ፤ ልጁም ፡
አሜስያስ ፡ በፋንታው ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በአካዝያስ ፡ ልጅ ፡ በኢዮ
አስ ፡ በሀያ ፡ ሦስተኛው ፡ ዓመት ፡ የኢዩ ፡ ልጅ ፡
ኢዮአካዝ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ በሰማርያ ፡ ነገሠ ፤
፪ አሥራ ፡ ሰባትም ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። በእግዚአብ
ሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረገ ÷ እስራኤል
ንም ፡ ያሳተውን ፡ የናባጥን ፡ ልጅ ፡ የኢዮርብዓ
ምን ፡ ኃጢአት ፡ ተከተለ ፤ ከእርስዋም ፡ አልራ
፫ ቀም ። የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ በእስራኤል ፡
ላይ ፡ ነደደ ÷ በዘመኑም ፡ ሁሉ ፡ በሶርያው ፡
ንጉሥ ፡ በአዛሄል ፡ እጅ ÷ በአዛሄልም ፡ ልጅ ፡
በወልደ ፡ አዴር ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣቸው ፡
፬ ነበር ። ኢዮአካዝም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመነ ፤
እግዚአብሔርም ፡ የሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ እስራኤ
ልን ፡ ያስጨነቀበትን ፡ ጭንቀት ፡ አይቶአልና ፡
፭ ሰማው ። እግዚአብሔርም ፡ ለእስራኤል ፡ ታዳጊ ፡
ሰጠ ÷ ከሶርያውያንም ፡ እጅ ፡ ዳኑ ፤ የእስራኤ
ልም ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ጊዜ ፡ በድን
፮ ኳናቸው ፡ ተቀመጡ ። ነገር ፡ ግን ፡ በእርስዋ ፡
ሄዱ ፡ እንጂ ፡ እስራኤልን ፡ ካሳተው ፡ ከኢዮ
ርብዓም ፡ ቤት ፡ ኃጢአት ፡ አልራቁም ፤ ደግ
ሞም ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀድ ፡ በሰማርያ ፡ ቆሞ ፡
፯ ቀረ ። ለኢዮአካዝም ፡ ከአምሳ ፡ ፈረሰኞች ÷
ከአሥርም ፡ ሰረገሎች ÷ ከአሥር ፡ ሺህም ፡ እግ
ረኞች ፡ በቀር ፡ ሕዝብ ፡ አልቀረለትም ፤ የሶ
ርያ ፡ ንጉሥ ፡ አጥፍቶአቸዋልና ÷ በአውድ
፰ ማም ፡ እንዳለ ፡ ዕብቅ ፡ አድቅቆአቸዋልና ። የቀ
ረውም ፡ የኢዮአካዝ ፡ ነገር ÷ ያደረገውም ፡
ሁሉ ÷ ጭከናውም ÷ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡
፱ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ኢዮ
አካዝም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ÷ በሰማር

ያም ፡ ቀበሩት ፤ ልጁም ፡ ዮአስ ፡ በፋንታው ፡ ነገሠ ።

፲ ፤ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮአስ ፡ በሠላሳ ፡ ሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ የኢዮአካዝ ፡ ልጅ ፡ ዮአስ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ በሰማርያ ፡ ነገሠ ፤ አሥራ ፡ ስድስትም ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። ፲፩ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረገ ፤ እስራኤልን ፡ በሳተው ፡ በናባጥ ፡ ልጅ ፡ በኢዮርብዓም ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ ሄደ ፡ እንጂ ፡ ከእርስዋ ፡ አልራቀም ። ፲፪ ፤ የቀረውም ፡ የዮአስ ፡ ነገር ÷ ያደረገውም ፡ ሁሉ ÷ ከይሁዳም ፡ ከአሜስያስ ፡ ጋር ፡ የተዋጋበት ፡ ጭከና ÷ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ፲፫ ፤ ዮአስም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ÷ ኢዮርብዓምም ፡ በዙፋኑ ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ፤ ዮአስም ፡ በሰማርያ ፡ ከእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ጋር ፡ ተቀበረ ።

፲፬ ፤ ኤልሳዕም ፡ በሚሞትበት ፡ በሽታ ፡ ታመመ ፤ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ዮአስ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ወርዶ ፡ በፊቱ ፡ አለቀሰና ፦ አባቴ ፡ ሆይ ÷ አባቴ ፡ ሆይ ÷ የእስራኤል ፡ ሰረገላና ፡ ፈረሰኞች ፡ አለ ። ፲፭ ፤ ኤልሳዕም ፦ ቀስትና ፡ ፍላጻዎች ፡ ውሰድ ፡ አለው ፤ ቀስቱንና ፡ ፍላጻዎችንም ፡ ወሰደ ። ፲፮ ፤ የእስራኤልንም ፡ ንጉሥ ፦ እጅህን ፡ በቀስቱ ፡ ላይ ፡ ጫን ፡ አለው ። እጁንም ፡ ጫነበት ፤ ኤልሳዕም ፡ እጁን ፡ በንጉሡ ፡ እጅ ፡ ላይ ፡ ጭኖ ፦ ፲፯ ፤ የምሥራቁን ፡ መስኮት ፡ ክፈት ፡ አለ ፤ ከፈተውም ። ኤልሳዕም ፦ ወርውር ፡ አለ ፤ ወረወረውም ። እርሱም ፦ የእግዚአብሔር ፡ መድኃኒት ፡ ፍላጻ ፡ ነው ፤ በሶርያ ፡ ላይ ፡ የመድኃኒት ፡ ፍላጻ ፡ ነው ፤ እስክታጠፋቸው ፡ ድረስ ፡ ሶርያውያንን ፡ በአፌቅ ፡ ትመታለህ ፡ አለ ። ፲፰ ፤ ደግሞም ፦ ፍላጻዎቹን ፡ ውሰድ ፡ አለው ፤ ወሰዳቸውም ። የእስራኤልንም ፡ ንጉሥ ፦ ምድሩን ፡ ምታው ፡ አለው ። ሦስት ፡ ጊዜም ፡ መትቶ ፡ ቆመ ። ፲፱ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ ተቆጥቶ ፦ አምስት ፡ ወይም ፡ ስድስት ፡ ጊዜ ፡ መትተኸው ፡ ኖሮ ፡ ሶርያን ፡ እስክታጠፋው ፡ ድረስ ፡ በመታኸው ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ ሶርያን ፡ ትመታለህ ፡ አለ ።

፳ ፤ ኤልሳዕም ፡ ሞተ ÷ ቀበሩትም ። ከሞዓብም ፡ አደጋ ፡ ጣዮች ፡ በየዓመቱ ፡ ወደ ፡ አገሩ ፡ ይገቡ ፡ ነበር ። ፳፩ ፤ ሰዎችም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሲቀብሩ ፡ አደጋ ፡ ጣዮችን ፡ አዩ ÷ ሬሳውንም ፡ በኤልሳዕ ፡ መቃብር ፡ ጣሉት ፤ የኤልሳዕንም ፡ አጥንት ፡ በነካ ፡ ጊዜ ፡ ሰውዮው ፡ ድኖ ፡ በእግሩ ፡ ቆመ ።

፳፪ ፤ የሶርያም ፡ ንጉሥ ፡ አዛሄል ፡ በኢዮአካዝ ፡ ፳፫ ፤ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ እስራኤልን ፡ አስጨነቀ ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ራራላቸው ÷ ማራቸውም ÷ ከአብርሃምና ፡ ከይስሐቅ ፡ ከያዕቆብም ፡ ጋር ፡ ስላደረገውም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ እነርሱን ፡ ተመለከተ ፤ ሊያጠፋቸውም ፡ አልወደደም ÷ ፈጽሞም ፡ ፳፬ ፤ ከፊቱ ፡ አልጣላቸውም ። የሶርያም ፡ ንጉሥ ፡ አዛሄል ፡ ሞተ ፤ ልጁም ፡ ወልደ ፡ አዴር ፡ በፋንታው ፡ ፳፭ ፤ ነገሠ ። አዛሄልም ፡ ከአባቱ ፡ ከኢዮአካዝ ፡ እጅ ፡ በሰልፍ ፡ የወሰዳቸውን ፡ ከተሞች ፡ የኢዮአካዝ ፡ ልጅ ፡ ዮአስ ፡ ከአዛሄል ፡ ልጅ ፡ ከወልደ ፡ አዴር ፡ እጅ ፡ ወሰደ ። ዮአስም ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ መታው ÷ የእስራኤልንም ፡ ከተሞች ፡ መለሰ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ ፤ በእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮአካዝ ፡ ልጅ ፡ በዮአስ ፡ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ የኢዮአስ ፡ ልጅ ፡ አሜስያስ ፡ ነገሠ ። ፪ ፤ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ሀያ ፡ ዘጠኝ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። እናቱም ፡ ዮዓዳን ፡ የተባለች ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ሴት ፡ ነበረች ። ፫ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አደረገ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አባቱ ፡ ኢዮአስ ፡ እንዳደረገ ፡ ሁሉ ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ አባቱ ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፡ አላደረገም ። ፬ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በኮረብቶቹ ፡ ላይ ፡ ያሉት ፡ መስገጃዎች ፡ አልተወገዱም ፤ ሕዝቡም ፡ ገና ፡ በኮረብቶች ፡ ላይ ፡ በሉት ፡ መስገጃዎች ፡ ይሠዋና ፡ ያጥን ፡ ነበር ። ፭ ፤ መንግሥቱም ፡ በጸናለት ፡ ጊዜ ፡ አባቱን ፡ የገደሉትን ፡ ባሪያዎች ፡ ገደለ ። ፮ ፤ በሙሴ ፡ ሕግ ፡ መጽሐፍም ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ÷ እግዚአብሔርም ፦ ሁሉ ፡ በኃጢአቱ ፡ ይሙት ፡ እንጂ ፡ አባቶች ፡ በልጆች ፡ አይሙቱ ÷ ልጆችም ፡ በአባቶች ፡ አይሙቱ ፡ ብሎ ፡ እንዳዘዘ ፡ የነፍሰ ፡ ገዳዮቹን ፡ ልጆች ፡ አልገደለም ። ፯ ፤ እርሱም ፡ በጨው ፡ ሸለቆ ፡ ከኤዶምያስ ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ሰው ፡ ገደለ ፤ ሴላን ፡ በሰልፍ ፡ ወስዶ ፡ ስምዋን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፤ ድረስ ፡ ዮቅትኤል ፡ ብሎ ፡ ጠራት ።

፰ ፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ አሜስያስ ፦ ና ፡ እርስ ፡ በርሳችን ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ እንተያይ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ኢዩ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢዮአካዝ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ዮአስ ፡ መልእክተኞችን ፡ ላከ ። ፱ ፤ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ዮአስ ፦ የሊባኖስ ፡ ኵርንችት ፦ ልጅህን ፡ ለልጄ ፡ ሚስት ፡ አድርገህ ፡ ስጠው ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ሊባኖስ ፡ ዝግባ ፡ ላከ ፤ የሊባኖስም ፡ አውሬ ፡ አልፎ ፡ ኵርንችቱን ፡ ረገጠ ። ፲ ፤ ኤዶምያስን ፡ በእውነት ፡ መታህ ÷ ልብህንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገህ ፤ በዚያ ፡ ተመካ ÷ በቤትህም ፡ ተቀመጥ ፤ አንተ ፡ ከይሁዳ ፡ ጋር ፡ ትወድቅ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ መከራ ፡ ትሻለህ ? ብሎ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ አሜስያስ ፡ ላከ ።

፲፩ ፤ አሜስያስ ፡ ግን ፡ አልሰማም ፤ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ዮአስ ፡ ወጣ ÷ እርሱና ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ አሜስያስም ፡ በይሁዳ ፡ ባለች ፡ በቤትሳሚስ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተያዩ ። ፲፪ ፤ ይሁዳም ፡ በእስራኤል ፡ ፊት ፡ ተመታ ፤ እያንዳንዱም ፡ ወደ ፡ ድንኳኑ ፡ ሸሸ ። ፲፫ ፤ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ዮአስ ፡ የይሁዳን ፡ ንጉሥ ፡ የአካዝያስን ፡ ልጅ ፡ የኢዮአስን ፡ ልጅ ፡ አሜስያስን ፡ በቤትሳሚስ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጣ ፤ የኢየሩሳሌምንም ፡ ቅጥር ፡ ከኤፍሬም ፡ በር ፡ ጀምሮ ፡

እስከ ፡ ማዕዘኑ ፡ በር ፡ ድረስ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ አፈረሰ ። ፲፬ ወርቁንና ፡ ብሩን ፡ ሁሉ ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ቤትና ፡ በንጉሡ ፡ ቤት ፡ መዛግብት ፡ የነበሩትን ፡ ዕቃዎች ፡ ሁሉ ÷ በመያዣም ፡ የተያዙትን ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ ሰማርያ ፡ ተመለሰ ።

፲፭ የቀረውም ፡ ያደረገው ፡ የዮአስ ፡ ነገር ÷ ጭከናውም ÷ ከይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ ከአሜስያስ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ተዋጋ ÷ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ፲፮ ዮአስም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ÷ በሰማርያም ፡ ከእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ጋር ፡ ተቀበረ ፤ ልጁም ፡ ኢዮርብዓም ፡ በፋንታው ፡ ነገሠ ።

፲፯ የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ የኢዮአስ ፡ ልጅ ፡ አሜስያስ ፡ ከእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ከኢዮአካዝ ፡ ልጅ ፡ ከዮአስ ፡ ሞት ፡ በኋላ ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ኖረ ። ፲፰ የቀረውም ፡ የአሜስያስ ፡ ነገር ፡ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ፲፱ በኢየሩሳሌምም ፡ የዓመፅ ፡ መሐላ ፡ አደረጉበት ÷ እርሱም ፡ ወደ ፡ ለኪሶ ፡ ኰበለለ ፤ በኋላውም ፡ ወደ ፡ ለኪሶ ፡ ላኩ ÷ በዚያም ፡ ገደሉት ። ፳ በፈረስም ፡ ጭነው ፡ አመጡት ÷ በኢየሩሳሌምም ፡ በዳዊት ፡ ከተማ ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ተቀበረ ። ፳፩ የይሁዳም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ የአሥራ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ የነበረውን ፡ ዓዛርያስን ፡ ወስዶ ፡ በአባቱ ፡ በአሜስያስ ፡ ፋንታ ፡ አነገሠው ። ፳፪ ንጉሡም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ካንቀላፋ ፡ በኋላ ÷ ኤላትን ፡ ሠርቶ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ መለሳት ።

፳፫ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮአስ ፡ ልጅ ፡ በአሜስያስ ፡ በአሥራ ፡ አምስተኛው ፡ ዓመት ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ የዮአስ ፡ ልጅ ፡ ኢዮርብዓም ፡ በሰማርያ ፡ መንገሥ ፡ ጀመረ ፤ አርባ ፡ አንድ ፡ ዓመትም ፡ ነገሠ ። ፳፬ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረገ ፤ እስራኤልንም ፡ ካሳተው ፡ ከናባጥ ፡ ልጅ ፡ ከኢዮርብዓም ፡ ኀጢአት ፡ ሁሉ ፡ አልራቀም ። ፳፭ የጋትሔፌር ፡ በነበረው ፡ በአማቴ ፡ ልጅ ፡ በባሪያው ፡ በነቢዩ ፡ በዮናስ ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ የእስራኤልን ፡ ድንበር ፡ ከሐማት ፡ መግቢያ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዓረባ ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፡ መለሰ ። ፳፮ የታሰረውና ፡ የተለቀቀውም ፡ እንደ ፡ ጠፋ ÷ እስራኤልንም ፡ የሚረዳ ፡ እንዳልነበረ ፡ እግዚአብሔር ፡ እጅግ ፡ የመረረውን ፡ የእስራኤልን ፡ ጭንቀት ፡ አየ ። ፳፯ እግዚአብሔርም ፡ የእስራኤልን ፡ ስም ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡ ይደመስስ ፡ ዘንድ ፡ አልተናገረም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በዮአስ ፡ ልጅ ፡ በኢዮርብዓም ፡ እጅ ፡ አዳናቸው ።

፳፰ የቀረውም ፡ የኢዮርብዓም ፡ ነገር ÷ ያደረገውም ፡ ሁሉ ÷ ጭከናውም ÷ እንደ ፡ ተዋጋም ÷ የይሁዳ ፡ የነበረውን ፡ ደማስቆንና ፡ ሐማትን ፡ ለእስራኤል ፡ እንደ ፡ መለሰ ÷ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ፳፱ ኢዮርብዓምም ፡ ከአባቶቹ ፡ ከእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፤ ልጁም ፡ ዘካርያ ፡ በፋንታው ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ በእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮርብዓም ፡ በሀያ ፡ ሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ የአሜስያስ ፡ ልጅ ፡ ዓዛርያስ ፡ ነገሠ ። ፪ መንገሥም ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የአሥራ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ አምሳ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡ ይኮልያ ፡ የተባለች ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ሴት ፡ ነበረች ። ፫ አባቱ ፡ አሜስያስ ፡ እንዳደረገው ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አደረገ ። ፬ ነገር ፡ ግን ፡ በኮረብቶች ፡ ላይ ፡ ያሉት ፡ መስገጃዎች ፡ አልተወገዱም ፤ ሕዝቡም ፡ ገና ፡ በኮረብቶች ፡ ላይ ፡ ባሉት ፡ መስገጃዎች ፡ ይሠዋና ፡ ያጥን ፡ ነበር ። ፭ እግዚአብሔርም ፡ ንጉሡን ፡ ቀሠፈው ÷ እስከ ፡ ሚሞትበትም ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ለምጻም ፡ ሆነ ÷ በተለየ ፡ ቤትም ፡ ይቀመጥ ፡ ነበር ፤ የንጉሡም ፡ ልጅ ፡ ኢዮአታም ፡ በንጉሥ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ ሠልጥኖ ፡ ለአገሩ ፡ ሕዝብ ፡ ይፈርድ ፡ ነበር ። ፮ የቀረውም ፡ የዓዛርያስ ፡ ነገር ÷ የሠራውም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ÷ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ፯ ዓዛርያስም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ÷ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ቀበሩት ፤ ልጁም ፡ ኢዮአታም ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

፰ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በዓዛርያስ ፡ በሠላሳ ፡ ስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ የኢዮርብዓም ፡ ልጅ ፡ ዘካርያ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ በሰማርያ ፡ ስድስት ፡ ወር ፡ ነገሠ ። ፱ አባቶቹም ፡ እንዳደረጉት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረገ ፤ እስራኤልን ፡ ካሳታቸው ፡ ከናባጥ ፡ ልጅ ፡ ከኢዮርብዓም ፡ ኀጢአት ፡ አልራቀም ። ፲ የኢያቤስም ፡ ልጅ ፡ ሰሎም ፡ ተማማለበት ÷ በይብልዓም ፡ መትቶ ፡ ገደለው ÷ በእርሱም ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ። ፲፩ የቀረውም ፡ የዘካርያ ፡ ነገር ÷ እነሆ ÷ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፎአል ። ፲፪ ለኢዩ ፦ ልጆችህ ፡ እስከ ፡ አራት ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ በእስራኤል ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ይቀመጣሉ ፡ ተብሎ ፡ የተነገረው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነበረ ፤ እንዲሁም ፡ ሆነ ።

፲፫ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በዖዝያን ፡ በሠላሳ ፡ ዘጠኝኛው ፡ ዓመት ፡ የኢያቤስ ፡ ልጅ ፡ ሰሎም ፡ ነገሠ ፤ በሰማርያም ፡ አንድ ፡ ወር ፡ ያህል ፡ ነገሠ ። ፲፬ የጋዲም ፡ ልጅ ፡ ምናሔም ፡ ከቴርሳ ፡ ወጥቶ ፡ ወደ ፡ ሰማርያ ፡ መጣ ÷ በሰማርያም ፡ የኢያቤስን ፡ ልጅ ፡ ሰሎምን ፡ መታ ÷ ገደለውም ፤ በእርሱም ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ። ፲፭ የቀረውም ፡ የሰሎም ፡ ነገር ÷ የተማማለውም ፡ ዓመፅ ÷ እነሆ ÷ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፎአል ። ፲፮ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ምናሔም ፡ ከቴርሳ ፡ ወጥቶ ፡ ቲፍሳን ፡ በእርስዋም ፡ ያሉትን ፡ ሁሉ ፡ ዳርቻ

ዋንም ፡ መታ ፤ ይከፍቱለትም ፡ ዘንድ ፡ አልወ
ደዱምና ፡ መታት ፤ በእርስዋም ፡ የነበሩትን ፡
እርጉዞች ፡ ሁሉ ፡ ቀደዳቸው ።

፲፯ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በዓዛርያስ ፡ በሠላሳ ፡ ዘጠ
ኝኛው ፡ ዓመት ፡ የጋዲ ፡ ልጅ ፡ ምናሔም ፡ በእስ
ራኤል ፡ ላይ ፡ መንገሥ ፡ ጀመረ ፤ በሰማርያም ፡
፲፰ አሥር ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡
ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረገ ፤ እስራኤልን ፡ ካሳተው ፡
ከናባጥ ፡ ልጅ ፡ ከኢዮርብዓም ፡ ኃጢአት ፡ አል
፲፱ ራቀም ። በዘመኑም ፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ፎሐ ፡
በምድሪቱ ፡ ላይ ፡ ወጣ ፤ ምናሔምም ፡ መንግ
ሥቱን ፡ በእጁ ፡ ያጸናለት ፡ ዘንድ ፡ የፎሐ ፡
እጅ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ እንዲሆን ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡
፳ መክሊት ፡ ብር ፡ ሰጠው ። ምናሔምም ፡ ብሩን ፡
ለአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ በእስራኤል ፡
ባለ ፡ ጠጎች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በእያንዳንዱ ፡ ላይ ፡
አምሳ ፡ ሰቅል ፡ ብር ፡ አስገብሮ ፡ አወጣ ። የአሦ
ርም ፡ ንጉሥ ፡ ተመለሰ ፥ በአገሪቱም ፡ አልተ
፳፩ ቀመጠም ። የቀረውም ፡ የምናሔም ፡ ነገር ፥
የሠራውም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፥ በእስራኤል ፡ ነገሥ
ታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን?
፳፪ ምናሔም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፤ ልጁም ፡
ፋቂስያስ ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

፳፫ በይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ በዓዛርያስ ፡ በአምሳ
ኛው ፡ ዓመት ፡ የምናሔም ፡ ልጅ ፡ ፋቂስያስ ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ በሰማርያ ፡ መንገሥ ፡ ጀመረ ፤
፳፬ ሁለት ፡ ዓመትም ፡ ነገሠ ። በእግዚአብሔርም ፡
ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረገ ፤ እስራኤልን ፡ ካሳ
ተው ፡ ከናባጥ ፡ ልጅ ፡ ከኢዮርብዓም ፡ ኃጢ
፳፭ አት ፡ አልራቀም ። የሠራዊቱም ፡ አለቃ ፡ የሮ
ሜልዩ ፡ ልጅ ፡ ፋቁሐ ፡ ተማማለበት ፥ በሰማ
ርያም ፡ በንጉሡ ፡ ቤት ፡ ግንብ ፡ ውስጥ ፡ ከአር
ጎብና ፡ ከአርያ ፡ ጋር ፡ መታው ፤ ከእርሱም ፡
ጋር ፡ አምሳ ፡ የገለዓድ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ ገደለ
፳፮ ውም ፥ በእርሱም ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ። የቀረውም ፡
የፋቂስያስ ፡ ነገር ፥ የሠራውም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፥
እነሆ ፥ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽ
ሐፍ ፡ ተጽፎአል ።

፳፯ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በዓዛርያስ ፡ በአምሳ ፡ ሁለ
ተኛው ፡ ዓመት ፡ የሮሜልዩ ፡ ልጅ ፡ ፋቁሐ ፡ በእ
ስራኤል ፡ ላይ ፡ በሰማርያ ፡ መንገሥ ፡ ጀመረ ፤
፳፰ ሀያ ፡ ዓመትም ፡ ነገሠ ። በእግዚአብሔርም ፡
ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረገ ፤ እስራኤልን ፡ ካሳ
ተው ፡ ከናባጥ ፡ ልጅ ፡ ከኢዮርብዓም ፡ ኃጢ
አት ፡ አልራቀም ።

፳፱ በእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ በፋቁሐ ፡ ዘመን ፡
የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ቴልጌልቴልፌልሶር ፡ መጥቶ ፡
ዒዮንና ፡ አቤልቤትመዓካን ፥ ያኖዋንም ፥ ቃዴ
ስንና ፡ አሶርንም ፥ ገለዓድንና ፡ ገሊላንም ፥ የንፍ
ታሌምን ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ወሰደ ፤ ወደ ፡ አሦርም ፡
፴ አፈለሳቸው ። በዖዝያንም ፡ ልጅ ፡ በኢዮአ
ታም ፡ በሀያኛው ፡ ዓመት ፡ የኤላ ፡ ልጅ ፡ ሆሴዕ ፡
በሮሜልዩ ፡ ልጅ ፡ በፋቁሐ ፡ ላይ ፡ ተማማለ ፥
መትቶም ፡ ገደለው ፥ በእርሱም ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

፴፩ የቀረውም ፡ የፋቁሐ ፡ ነገር ፥ የሠራውም ፡ ሥራ ፡
ሁሉ ፥ እነሆ ፥ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡
መጽሐፍ ፡ ተጽፎአል ።

፴፪ በእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ በሮሜልዩ ፡ ልጅ ፡ በፋ
ቁሐ ፡ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡
፴፫ የዖዝያን ፡ ልጅ ፡ ኢዮአታም ፡ ነገሠ ። መንገሥ ፡
በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ጕል
ማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ አሥራ ፡ ስድስት ፡
ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱ ፡ የሳዶቅ ፡ ልጅ ፡ ኢየሩሳ ፡
፴፬ ነበረች ። በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡
አደረገ ፤ አባቱ ፡ ዖዝያን ፡ እንዳደረገ ፡ ሁሉ ፡
፴፭ እንዲሁ ፡ አደረገ ። ነገር ፡ ግን ፡ በኮረብቶች ፡
ላይ ፡ ያሉት ፡ መስገጃዎች ፡ አልተወገዱም ፤
ሕዝቡም ፡ ገና ፡ በኮረብቶች ፡ ላይ ፡ ባሉት ፡
መስገጃዎች ፡ ይሠዋና ፡ ያጥን ፡ ነበር ። እርሱም ፡
የላይኛውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ በር ፡
፴፮ ሠራ ። የቀረውም ፡ የኢዮአታም ፡ ነገር ፥ የሠ
ራውም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፥ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡
፴፯ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? በዚ
ያም ፡ ወራት ፡ እግዚአብሔር ፡ የሶርያን ፡ ንጉሥ ፡
ረአሶንንና ፡ የሮሜልዩን ፡ ልጅ ፡ ፋቁሔን ፡ በይ
፴፰ ሁዳ ፡ ላይ ፡ መስደድ ፡ ጀመረ ። ኢዮአታም ፡
ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በአባቱም ፡ በዳ
ዊት ፡ ከተማ ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ተቀበረ ፤ ልጁም ፡
አካዝ ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ በሮሜልዩ ፡ ልጅ ፡ በፋቁሐ ፡ በአሥራ ፡ ሰባ
ተኛው ፡ ዓመት ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ የኢዮአ
፪ ታም ፡ ልጅ ፡ አካዝ ፡ ነገሠ ። አካዝ ፡ መንገሥ ፡
በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፤
በኢየሩሳሌምም ፡ አሥራ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡
ነገሠ ፤ እንደ ፡ አባቱም ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፡ በአም
ላኩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አላ
፫ ደረገም ። ነገር ፡ ግን ፡ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡
መንገድ ፡ ሄደ ፤ ደግሞም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእ
ስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ እንዳሳደዳቸው ፡
እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ርኵሰት ፡ ልጁን ፡ በእሳት ፡ አሳ
፬ ለፈው ። በመስገጃዎችና ፡ በኮረብቶቹ ፡ ላይ ፡
በለመለመውም ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ በታች ፡ ይሠዋና ፡
ያጥን ፡ ነበር ።

፭ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ የሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ ረአሶንና ፡
የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ የሮሜልዩ ፡ ልጅ ፡ ፋቁሐ ፡
ሊዋጉ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጡ ፤ አካዝንም ፡
ከበቡት ፥ ሊያሸንፉት ፡ ግን ፡ አልቻሉም ።
፮ በዚያም ፡ ዘመን ፡ የሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ ረአሶን ፡
ኤላትን ፡ ወደ ፡ ሶርያ ፡ መለሰ ፥ አይሁድንም ፡
ከኤላት ፡ አሳደደ ፤ ኤዶማውያንም ፡ ወደ ፡
ኤላት ፡ መጥተው ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በእር
ስዋ ፡ ተቀምጠዋል ።

፯ አካዝም ፡— እኔ ፡ ባሪያህና ፡ ልጅህ ፡ ነኝ ፤
መጥተህ ፡ ከተነሡብን ፡ ከሶርያ ፡ ንጉሥና ፡ ከእ
ስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ አድነኝ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡
አሦር ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ቴልጌልቴልፌልሶር ፡

፰ መልእክተኞችን ፡ ላከ ። አካዝም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤትና ፡ በንጉሡ ፡ ቤት ፡ መዛግብት ፡ የተገኘውን ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ አሦር ፡ ንጉሥ ፡ ገጸ ፡ በረከት ፡ አድርጎ ፡ ሰደደው ። ፱ የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ ሰማው ፤ የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ በደማስቆ ፡ ላይ ፡ ወጣበት ፡ ወሰዳትም ፥ ሕዝብዋንም ፡ ወደ ፡ ቂር ፡ አፈለሳቸው ፥ ረአሶንንም ፡ ገደለ ።

፲ ንጉሡም ፡ አካዝ ፡ የአሦርን ፡ ንጉሥ ፡ ቴልጌልቴልፌልሶርን ፡ ሊገናኘው ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ ሄደ ፤ በደማስቆ ፡ የነበረውን ፡ መሠዊያ ፡ አየ ፤ ንጉሡም ፡ አካዝ ፡ የመሠዊያውን ፡ ምሳሌና ፡ የአሠራሩን ፡ መልክ ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ወደ ፡ አርያ ፡ ላከው ። ፲፩ ካህኑም ፡ አርያ ፡ መሠዊያ ፡ ሠራ ፤ ንጉሡ ፡ አካዝ ፡ ከደማስቆ ፡ ልኮ ፡ እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ ካህኑ ፡ አርያ ፡ ንጉሡ ፡ አካዝ ፡ ፲፪ ከደማስቆ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ ሠራው ። ንጉሡም ፡ ከደማስቆ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ መሠዊያውን ፡ አየ ፤ ንጉሡም ፡ ወደ ፡ መሠዊያው ፡ ቀርቦ ፡ በእ ፲፫ ርሱ ፡ ላይ ፡ ወጣ ። በመሠዊያውም ፡ ላይ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የእህሉን ፡ ቍርባን ፡ አሳረገ ፥ የመጠጡንም ፡ ቍርባን ፡ አፈሰሰ ፥ ፲፬ የደኅንነቱንም ፡ መሥዋዕት ፡ ደም ፡ ረጨ ። በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ የነበረውን ፡ የናሱን ፡ መሠዊያ ፡ ከመቅደሱ ፡ ፊት ፡ ከመሠዊያውና ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ መካከል ፡ ፈቀቅ ፡ አድርጎ ፡ በመሠዊያው ፡ አጠገብ ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ፲፭ አኖረው ። ንጉሡም ፡ አካዝ ፡— የሚቃጠለውን ፡ የጥዋት ፡ መሥዋዕት ፥ የማታውንም ፡ የእህሉን ፡ ቍርባን ፥ የንጉሡንም ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የእህሉን ፡ ቍርባን ፥ ለአገሩም ፡ ሕዝብ ፡ የሚሆን ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የእህሉን ፡ የመጠጡንም ፡ ቍርባን ፡ በታላቁ ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ አቅርብ ፤ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ ደም ፡ ሁሉ ፡ የሌላ ፡ መሥዋዕቱንም ፡ ደም ፡ ሁሉ ፡ ርጭበት ፤ የናሱ ፡ መሠዊያ ፡ ግን ፡ እኔ ፡ እጠይቅበት ፡ ዘንድ ፡ ይሁን ፡ ፲፮ ብሎ ፡ ካህኑን ፡ አርያን ፡ አዘዘው ። ካህኑ ፡ አርያ ፡ ንጉሡ ፡ አካዝ ፡ እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ አደረገ ።

፲፯ ንጉሡም ፡ አካዝ ፡ የመቀመጫዎችን ፡ ክፈፍ ፡ ቈረጠ ፥ ከእነርሱም ፡ የመታጠቢያውን ፡ ሰኖች ፡ ወሰደ ፤ ኵሬውንም ፡ ከበታቹ ፡ ከነበሩት ፡ ከናሱ ፡ በሬዎች ፡ አወረደው ፥ በጠፍጣፋውም ፡ ድን ፲፰ ጋይ ፡ ላይ ፡ አኖረው ። በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ የዙፋኑን ፡ መሠረት ፡ ሠራ ፤ ስለ ፡ አሦርም ፡ ንጉሥ ፡ በውጭ ፡ ያለውን ፡ የንጉሡን ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አዞረው ። ፲፱ የቀረውም ፡ አካዝ ፡ ያደረገው ፡ ነገር ፡ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደ ፳ ለምን ? አካዝም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ተቀበረ ፤ ልጁም ፡ ሕዝቅያስ ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በአካዝ ፡ በአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ የኤላ ፡ ልጅ ፡ ሆሴዕ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ በሰማርያ ፡ ንጉሥ ፡ ሆነ ፤ ዘጠኝ ፡ ዓመትም ፡ ነገሠ ። ፪ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረገ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ አስቀድሞ ፡ እንደ ፡ ነበሩት ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ አይደለም ። ፫ የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ ስልምናሶር ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ወጣ ፤ ሆሴዕም ፡ ተገዛለት ፥ ግብርም ፡ አመጣለት ። ፬ የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ በሆሴዕ ፡ ላይ ፡ ዓመፅ ፡ አገኘ ፤ መልእክተኞችን ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ሴጎር ፡ ልኮ ፡ ነበርና ፤ እንደ ፡ ልማዱም ፡ በየዓመቱ ፡ ለአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ግብር ፡ አልሰጠምና ፤ ስለዚህ ፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ይዞ ፡ በወህኒ ፡ ቤት ፡ አሰረው ። ፭ የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ወጣ ፥ ወደ ፡ ሰማርያም ፡ ወጥቶ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ከበባት ። ፮ በሆሴዕ ፡ በዘጠኝኛው ፡ ዓመት ፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ሰማርያን ፡ ወሰደ ፥ እስራኤልንም ፡ ወደ ፡ አሦር ፡ አፈለሰ ፥ በአላሔና ፡ በአቦር ፡ በጎዛንም ፡ ወንዝ ፡ በሜዶንም ፡ ከተሞች ፡ አኖራቸው ።

፯ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ከፈርዖን ፡ እጅ ፥ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ያወጣቸውን ፡ አምላካቸውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ በድለው ፡ ነበርና ፥ ሌሎችንም ፡ አማልክት ፡ አምልከው ፡ ነበርና ፥ ፰ እግዚአብሔርም ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ በሰደዳቸው ፡ በአሕዛብ ፡ ሥርዓት ፥ የእስራኤልም ፡ ነገሥታት ፡ ባደረጉት ፡ ሥርዓት ፡ ሄደው ፡ ነበርና ፡ እንደዚህ ፡ ሆነ ። ፱ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በአምላካቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ቅን ፡ ያልሆነን ፡ ነገር ፡ በስውር ፡ አደረጉ ፤ በከተሞቻቸውም ፡ ሁሉ ፡ ከዘበኞች ፡ ግንብ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ተመሸገች ፡ ከተማ ፡ ድረስ ፡ በከፍታሞቹ ፡ ላይ ፡ መስገጃዎችን ፡ ሠሩ ። ፲ በረጃጅሙ ፡ ኮረብታ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በለመለመውም ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ታች ፡ ሐውልቶችንና ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶችን ፡ ተከሉ ፤ ፲፩ እግዚአብሔርም ፡ ከፊታቸው ፡ ያወጣቸው ፡ አሕዛብ ፡ እንዳደረጉት ፥ በኮረብቶቹ ፡ መስገጃዎች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያጥኑ ፡ ነበር ፤ እግዚአብሔርንም ፡ ያስቈጡ ፡ ዘንድ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረጉ ፤ ፲፪ እግዚአብሔርም ፡ የከለከላቸውን ፡ ጣዖቶች ፡ አመለኩ ። ፲፫ እግዚአብሔርም ፡— ከክፉ ፡ መንገዳችሁ ፡ ተመለሱ ፤ ለአባቶቻችሁም ፡ እንዳዘዝሁት ፥ በባሪያዎቼ ፡ በነቢያት ፡ የላክሁላችሁን ፡ ትእዛዜንና ፡ ሥርዓቴን ፡ ሕጌንም ፡ ሁሉ ፡ ጠብቁ ፡ ብሎ ፡ በነቢዩ ፡ ሁሉና ፡ በባለ ፡ ራእዩ ፡ አፍ ፡ ሁሉ ፡ በእስራኤልና ፡ በይሁዳ ፡ መሰከረ ። ፲፬ ነገር ፡ ግን ፡ አምላካቸውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዳላመኑ ፡ እንደ ፡ አባቶቻቸው ፡ አንገት ፡ አንገታቸውን ፡ አደነደኑ ፡ እንጂ ፡ አልሰሙም ።

፲፭፤ ሥርዓቱንም ፡ ከአባቶቻቸውም ፡ ጋር ፡ ያደረገ
ውን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ÷ ያጸናላቸውንም ፡ ምስክ
ሩን ፡ ናቁ ፤ ከንቱ ፡ ነገርንም ፡ ተከተሉ ÷ ምና
ምንቴዎችም ፡ ሆኑ ÷ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡
እነርሱ ፡ እንዳይሠሩ ፡ ያዘዛቸውን ፡ በዙሪያ
፲፮፤ ቸው ፡ ያሉትን ፡ አሕዛብን ፡ ተከተሉ ። የአም
ላካቸውንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡
ተዉ ÷ ቀልጠው ፡ የተሠሩትንም ፡ የሁለቱን ፡
እምቦሶች ፡ ምስሎች ፡ አደረጉ ÷ የማምለኪያ ፡
ዐፀድንም ፡ ተከሉ ÷ ለሰማይም ፡ ሠራዊት ፡
፲፯፤ ሁሉ ፡ ሰገዱ ÷ በኣልንም ፡ አመለኩ ። ወንዶ
ችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ በእሳት ፡ አሳለፉ
አቸው ÷ ምዋርተኞችና ፡ አስማተኞችም ፡
ሆኑ ÷ ያስቈጡትም ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ለማድረግ ፡ ራሳቸውን ፡
፲፰፤ ሸጡ ። ስለዚህም ፡ እግዚአብሔር ፡ በእስራኤል ፡
ላይ ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ÷ ከፊቱም ፡ ጣላቸው ፤
ከይሁዳም ፡ ነገድ ፡ ብቻ ፡ በቀር ፡ ማንም ፡ አል
ቀረም ።

፲፱፤ ይሁዳም ፡ ደግሞ ፡ እስራኤል ፡ ባደረጋት ፡
ሥርዓት ፡ ሄደ ፡ እንጂ ፡ የአምላኩን ፡ የእግዚአ
፳፤ ብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ አልጠበቀም ። እግዚአብ
ሔርም ፡ የእስራኤልን ፡ ዘር ፡ ሁሉ ፡ ጣላ ÷ አስ
ጨንቃቸውም ÷ ከፊቱም ፡ እስኪጥላቸው ፡
ድረስ ፡ በበዝባዦች ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ።
፳፩፤ እስራኤልንም ፡ ከዳዊት ፡ ቤት ፡ ለየ ፤ የናባጥ
ንም ፡ ልጅ ፡ ኢዮርብዓምን ፡ አነገሡ ፤ ኢዮርብ
ዓምም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከመከተል ፡ እስራኤ
ልን ፡ መለሰ ÷ ታላቅም ፡ ኃጢአት ፡ አሠራቸው ።
፳፪፤፳፫፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ኢዮርብዓም ፡ ባደረ
ገው ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ ሄዱ ፤ እግዚአብሔርም ፡
በባሪያዎቹ ፡ በነቢያቱ ፡ ሁሉ ፡ አፍ ፡ እንደ ፡
ተናገረው ፡ እስራኤልን ፡ ከፊቱ ፡ እስኪያወጣ ፡
ድረስ ፡ ከእርስዋ ፡ አልራቁም ። እስራኤልም ፡
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ከምድሩ ፡ ወደ ፡ አሦር ፡
ፈለሰ ።

፳፬፤ የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ ከባቢሎንና ፡ ከኩታ ፡
ከአዋና ፡ ከሐማት ፡ ከሴፈርዋይም ፡ ሰዎችን ፡
አመጣ ÷ በእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ፋንታ ፡ በሰማ
ርያ ፡ ከተሞች ፡ አኖራቸው ፤ ሰማርያንም ፡ ወረ
፳፭፤ ሱአት ፤ በከተሞችዋም ፡ ተቀመጡ ። በዚያም ፡
መቀመጥ ፡ በጀመሩ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡
አይፈሩትም ፡ ነበር ፤ እግዚአብሔርም ፡ አንበ
ሶች ፡ ሰደደባቸው ÷ ይገድሉአቸውም ፡ ነበር ።
፳፮፤ ስለዚህም ፡ ለአሦር ፡ ንጉሥ ፡— ያፈለስኻቸው ÷
በሰማርያም ፡ ከተሞች ፡ ያኖርኻቸው ፡ የአገ
ሩን ፡ አምላክ ፡ ወግ ፡ አላወቁም ፤ የአገሩን ፡
አምላክ ፡ ወግ ፡ አላወቁምና ፡ አንበሶችን ፡ ሰድ
ዶባቸዋል ÷ እነሆም ÷ ገደሉአቸው ፡ ብለው ፡
ተናገሩት ።

፳፯፤ የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡— ከዚያ ፡ ካመጣችኋ
ቸው ፡ ካህናት ፡ አንዱን ፡ ውሰዱ ፤ ሄዶም ፡
በዚያ ፡ ይቀመጥ ÷ የአገሩንም ፡ አምላክ ፡ ወግ ፡
፳፰፤ ያስተምራቸው ፡ ብሎ ፡ አዘዘ ። ከሰማርያም ፡
ካፈለሱአቸው ፡ ካህናት ፡ አንዱ ፡ መጥቶ ፡ በቤ
ቴል ፡ ተቀመጠ ÷ እግዚአብሔርንም ፡ እንዴት ፡
፳፱፤ እንዲፈሩት ፡ ያስተምራቸው ፡ ነበር ። በየሕዝ
ባቸውም ፡ አምላካቸውን ፡ አደረጉ ÷ ሰምራው
ያንም ፡ በሠሩት ፡ በኮረብታው ፡ መስገጃዎች ፡
ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ በሚኖሩበት ፡ ከተሞቻቸው ፡ አኖ
፴፤ ሩአቸው ። የባቢሎንም ፡ ሰዎች ፡ ሱኮትበኖ
ትን ፡ ሠሩ ፤ የኩታም ፡ ሰዎች ፡ ኤርጌልን ፡ ሠሩ ፤
፴፩፤ የሐማትም ፡ ሰዎች ፡ አሲማትን ፡ ሠሩ ፤ አዋው
ያንም ፡ ኤልባዝርንና ፡ ተርታቅን ፡ ሠሩ ፤ የሴፈ
ርዋይም ፡ ሰዎችም ፡ ለሴፈርዋይም ፡ አማልክት ፡
ለአድራሜሌክና ፡ ለአነሜሌክ ፡ ልጆቻቸውን ፡
፴፪፤ በእሳት ፡ ያቃጥሉ ፡ ነበር ። እግዚአብሔርንም ፡
ይፈሩ ፡ ነበር ÷ ከመካከላቸውም ፡ ለኮረብታው ፡
መስገጃዎች ፡ ካህናት ፡ አደረጉ ÷ በኮረብታ
፴፫፤ ውም ፡ መስገጃዎች ፡ ይሠዉ ፡ ነበር ። እግዚአ
ብሔርንም ፡ ሲፈሩ ፡ ከመካከላቸው ፡ እንደ ፡
ፈለሱት ፡ እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ልማድ ፡ አምላካቸ
ውን ፡ ያመልኩ ፡ ነበር ።

፴፬፤ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ ቀደመው ፡ ልማድ ፡
ያደርጋሉ ፤ እግዚአብሔርንም ፡ አይፈሩም ÷
እግዚአብሔርም ፡ እስራኤል ፡ ብሎ ፡ የጠራ
ውን ፡ የያዕቆብን ፡ ልጆች ፡ እንዳዘዛቸው ፡
ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ ሕግና ፡ ትእዛዝም ፡ አያደ
፴፭፤ ርጉም ። እግዚአብሔርም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡
ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረገ ÷ እንዲህም ፡ ብሎ ፡ አዘዛ
ቸው ፡— ሌሎችን ፡ አማልክት ፡ አትፍሩ ÷ አት
ስገዱላቸው ÷ አታምልኩአቸው ÷ አትሠዉ
፴፮፤ ላቸው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በታላቅ ፡ ኃይል ፡ በተዘረጋ
ችም ፡ ክንድ ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ያወጣችሁን ፡
እግዚአብሔር ፡ እርሱን ፡ ፍሩ ÷ ለእርሱም ፡
፴፯፤ ስገዱ ÷ ለእርሱም ፡ ሠዉ ፤ የጻፈላችሁንም ፡
ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ ሕግና ፡ ትእዛዝም ፡ ለዘላ
ለም ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ጠብቁ ፤ ሌሎችንም ፡
፴፰፤ አማልክት ፡ አትፍሩ ። ከእናንተም ፡ ጋር ፡ ያደ
ረግሁትን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አትርሱ ፤ ሌሎችንም ፡
፴፱፤ አማልክት ፡ አትፍሩ ። አምላካችሁን ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ ፍሩ ፤ እርሱም ፡ ከጠላቶቻችሁ ፡
፵፤ ሁሉ ፡ እጅ ፡ ያድናችኋል ። ነገር ፡ ግን ፡ እንደ ፡
ቀደመው ፡ ልማዳቸው ፡ አደረጉ ፡ እንጂ ፡ አል
፵፩፤ ሰሙም ። እነዚህም ፡ አሕዛብ ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ ይፈሩ ፡ ነበር ፤ ደግሞም ፡ የተቀረጹ ፡ ምስ
ሎቻቸውን ፡ ያመልኩ ፡ ነበር ፤ ልጆቻቸውም ፡
የልጅ ፡ ልጆቻቸውም ፡ አባቶቻቸው ፡ እንዳደ
ረጉ ፡ እንዲሁ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ያደርጋሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ በኤላ ፡
ልጅ ፡ በሆሴዕ ፡ በሦስተኛው ፡ ዓመት ፡ የይሁዳ ፡
፪፤ ንጉሥ ፡ የአካዝ ፡ ልጅ ፡ ሕዝቅያስ ፡ ነገሠ ። መን
ገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡
ጕልማሳ ፡ ነበረ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ሀያ ፡ ዘጠኝ ፡
ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡ የዘካርያስ ፡ ልጅ ፡
፫፤ አቡ ፡ ነበረች ። እርሱም ፡ አባቱ ፡ ዳዊት ፡ እን

ዳደረገው ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቅን ፡
፬ ነገርን ፡ አደረገ ። በኮረብታም ፡ ያሉትን ፡ መስ
ገጃዎች ፡ አስወገደ ፥ ሐውልቶችንም ፡ ቀለጣ
ጠመ ፥ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶቹንም ፡ ቈረጠ ፤ የእ
ስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እስከዚህ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡
ያጥኑለት ፡ ነበርና ፡ ሙሴ ፡ የሠራውን ፡ የናሱን ፡
እባብ ፡ ሰባበረ ፤ ስሙንም ፡ ነሑሽታን ፡ ብሎ ፡
፭ ጠራው ። በእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ታመነ ፤ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ከእርሱም ፡
በፊት ፡ ከነበሩት ፡ ከይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡
፮ እርሱን ፡ የሚመስል ፡ አልነበረም ። ከእግዚአ
ብሔርም ፡ ጋር ፡ ተጣበቀ ፥ እርሱንም ፡ ከመከ
ተል ፡ አልራቀም ፥ እግዚአብሔርም ፡ ለሙሴ ፡
፯ ያዘዘውን ፡ ትእዛዛቱን ፡ ጠበቀ ። እግዚአብሔ
ርም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፥ የሚሄድበትም ፡
መንገድ ፡ ተከናወነለት ፤ በአሦርም ፡ ንጉሥ ፡
፰ ላይ ፡ ዐመፀ ፥ አልገበረለትም ። ፍልስጥኤማ
ውያንንም ፡ እስከ ፡ ጋዛና ፡ እስከ ፡ ዳርቻዋ ፡
ድረስ ፥ ከዘበኞች ፡ ግንብ ፡ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ምሽጉ ፡ ከተማ ፡ ድረስ ፡ መታ ።

፱ በንጉሡ ፡ በሕዝቅያስ ፡ በአራተኛው ፡ ዓመት ፥
በእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ በኤላ ፡ ልጅ ፡ በሆሴዕ ፡
በሰባተኛው ፡ ዓመት ፥ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ስል
ምናሶር ፡ ወደ ፡ ሰማርያ ፡ ወጣ ፥ ከበባትም ።
፲ ከሦስት ፡ ዓመት ፡ በኋላም ፡ ወሰዳት ፤ በሕዝቅ
ያስ ፡ በስድስተኛው ፡ ዓመት ፥ በእስራኤል ፡
ንጉሥ ፡ በሆሴዕ ፡ በዘጠኝኛው ፡ ዓመት ፥ ሰማ
፲፩ ርያ ፡ ተያዘች ። የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ እስራኤልን ፡
ወደ ፡ አሦር ፡ አፈለሰ ፥ በአላሔና ፡ በአቦር ፡
በጎዛንም ፡ ወንዝ ፡ በሜዶንም ፡ ከተሞች ፡ አኖ
፲፪ ራቸው ፤ የአምላካቸውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ቃል ፡ አልሰሙምና ፥ ቃል ፡ ኪዳኑንም ፡ አፍ
ርሰዋልና ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ባሪያ ፡ ሙሴ ፡
ያዘዘውን ፡ ሁሉ ፡ አልሰሙምና ፥ አላደረጉምና ።

፲፫ በንጉሡም ፡ በሕዝቅያስ ፡ በአሥራ ፡ አራተ
ኛው ፡ ዓመት ፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ሰናክሬም ፡
ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ወደ ፡ ተመሸጉት ፡ ከተሞች ፡
፲፬ ሁሉ ፡ ወጣ ፥ ወሰዳቸውም ። የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡
ሕዝቅያስ ፡— በድያለሁ ፥ ከእኔ ፡ ተመለስ ፤ የም
ትጭንብኝን ፡ ሁሉ ፡ እሸከማለሁ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡
አሦር ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ለኪሶ ፡ላከ ። የአሦርም ፡
ንጉሥ ፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በሕዝቅያስ ፡ ላይ ፡
ሦስት ፡ መቶ ፡ መክሊት ፡ ብርና ፡ ሠላሳ ፡ መክ
፲፭ ሊት ፡ ወርቅ ፡ ጫነበት ። ሕዝቅያስም ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ቤትና ፡ በንጉሡ ፡ ቤት ፡ መዛግ
፲፮ ብት ፡ የተገኘውን ፡ ብር ፡ ሁሉ ፡ ሰጠው ። በዚ
ያን ፡ ጊዜም ፡ ሕዝቅያስ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ መቅ
ደስ ፡ ደጆችና ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ሕዝቅያስ ፡
ከለበጣቸው ፡ መቃኖች ፡ ወርቁን ፡ ቈረጠ ፥ ለአ
ሦርም ፡ ንጉሥ ፡ ሰጠው ።

፲፯ የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ ተርታንንና ፡ ራፌስን ፡
ራፋስቂስንም ፡ ከብዙ ፡ ሠራዊት ፡ ጋር ፡ ከለኪሶ ፡
ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ሕዝቅያስ ፡ ወደ ፡ ኢየሩ
ሳሌም ፡ ላከ ። ወጥተውም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
መጡ ፤ በመጡም ፡ ጊዜ ፡ በአጣቢው ፡ እርሻ ፡
መንገድ ፡ ባለችው ፡ በላይኛይቱ ፡ ኵሬ ፡ መስኖ ፡
፲፰ አጠገብ ፡ ቆሙ ። ንጉሡንም ፡ ጠሩ ፤ የቤቱም ፡
አዛዥ ፡ የኬልቅያስ ፡ ልጅ ፡ ኤልያቄም ፡ ጸሐፊ
ውም ፡ ሳምናስ ፡ ታሪክ ፡ ጸሐፊውም ፡ የአሳፍ ፡
ልጅ ፡ ዮአስ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ወጡ ።

፲፱ ራፋስቂስም ፡ አላቸው ፡— ለሕዝቅያስ ፡ እን
ዲህ ፡ ብላችሁ ፡ ንገሩት ፡— ታላቁ ፡ የአሦር ፡
ንጉሥ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ይህ ፡ የምትታ
፳ መንበት ፡ መተማመኛ ፡ ምንድር ፡ ነው ? የከን
ፈር ፡ ቃል ፡ ለሰልፍ ፡ ምክርና ፡ ኃይል ፡ እንደ
ሚሆን ፡ ትናገራለህ ፤ አሁንም ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡
፳፩ ያመፅኸው ፡ በማን ፡ ተማምነህ ፡ ነው ? እነሆ ፥
በዚህ ፡ በተቀጠቀጠ ፡ በሸምበቆ ፡ በትር ፡ በግ
ብጽ ፡ ትታመናለህ ፤ ሰው ፡ ቢመረኰዘው ፡ ተሰ
ብሮ ፡ በእጁ ፡ ይገባል ፡ ያቈስለውማል ፤ የግብጽ ፡
ንጉሥ ፡ ፈርዖን ፡ ለሚታመኑበት ፡ ሁሉ ፡ እን
፳፪ ዲሁ ፡ ነው ። እናንተም ፡— በአምላካችን ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ እንታመናለን ፡ ብትሉኝ ፥ ሕዝቅ
ያስ ፡ ይሁዳንና ፡ ኢየሩሳሌምን ፡— በኢየሩሳ
ሌም ፡ ባለው ፡ በዚህ ፡ መሠዊያ ፡ ፊት ፡ ስገዱ ፡
ብሎ ፡ የኮረብታ ፡ መስገጃዎቹንና ፡ መሠዊያዎ
፳፫ ቹን ፡ ያስፈረሰ ፡ ይህ ፡ አይደለምን ? አሁን ፡ እንግ
ዲህ ፡ ከጌታዬ ፡ ከአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ጋር ፡ ተወራ
ረድ ፥ የሚቀመጡባቸውንም ፡ ሰዎች ፡ ማግ
ኘት ፡ ቢቻልህ ፡ እኔ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ፈረሶች ፡
፳፬ እሰጥሃለሁ ። ስለ ፡ ሰረገሎችና ፡ ስለ ፡ ፈረሰ
ኞች ፡ በግብጽ ፡ ስትታመን ፥ ከጌታዬ ፡ ባሪያ
ዎች ፡ የሚያንሰውን ፡ የአንዱ ፡ አለቃ ፡ ፊት ፡
፳፭ ትቃወም ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ይቻልሃል ? አሁን ፡
በውኑ ፡ ያለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ ይህን ፡
ስፍራ ፡ አጠፋ ፡ ዘንድ ፡ ወጥቻለሁን ? እግዚአ
ብሔር ፡— ወደዚች ፡ አገር ፡ ወጥተህ ፡ አጥፋት ፡
አለኝ ።

፳፮ የኬልቅያስም ፡ ልጅ ፡ ኤልያቄም ፡ ሳምናስም ፡
ዮአስም ፡ ራፋስቂስን ፡— እኛ ፡ እንሰማለንና ፡
እባክህ ፥ በሶርያ ፡ ቋንቋ ፡ ለባሪያዎችህ ፡ ተና
ገር ፤ በቅጥርም ፡ ላይ ፡ ባለው ፡ ሕዝብ ፡ ጆሮ ፡
፳፯ በአይሁድ ፡ ቋንቋ ፡ አትናገረን ፡ አሉት ። ራፋ
ስቂስ ፡ ግን ፡— ጌታዬ ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ እናገር ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ አንተና ፡ ወደ ፡ ጌታህ ፡ ልኮኛ
ልን ? ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ኵሳቸውን ፡ ይበሉ ፡
ዘንድ ፡ ሽንታቸውንም ፡ ይጠጡ ፡ ዘንድ ፡ በቅ
ጥር ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ተቀመጡት ፡ ሰዎች ፡ አይደ
፳፰ ለምን ? አላቸው ። ራፋስቂስም ፡ ቆሞ ፡ በታ
ላቅ ፡ ድምፅ ፡ በአይሁድ ፡ ቋንቋ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
ጮኸ ፡— የታላቁን ፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ቃል ፡
፳፱ ስሙ ፤ ንጉሡ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ከእጁ ፡
ያድናችሁ ፡ ዘንድ ፡ አይችልምና ፡ ሕዝቅያስ ፡
፴ አያታልላችሁ ፤ ሕዝቅያስም ፡— እግዚአብ
ሔር ፡ በእርግጥ ፡ ያድነናል ፥ ይህችም ፡ ከተማ ፡
በአሦር ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ አትሰጥም ፡ ብሎ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ እንድትታመኑ ፡ አያድርጋችሁ ።
፴፩ ሕዝቅያስንም ፡ አትስሙ ፤ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡

እንዲህ ፡ ይላል ፡— ከእኔ ፡ ጋር ፡ ታረቁ ÷ ወደ ፡
እኔም ፡ ውጡ ÷ እያንዳንዳችሁም ፡ ከወይናች
ሁና ፡ ከበለሳችሁ ፡ ብሉ ፡ ከጕድጓዳችሁም ፡
፴፪ ውኃ ፡ ጠጡ ፤ ይህም ፡ መጥቼ ፡ ምድራችሁን ፡
ወደምትመስለው ፡ ምድር ÷ እህልና ፡ የወይን ፡
ጠጅ ÷ እንጀራና ፡ ወይን ÷ ወይራና ፡ ማር ፡ ወዳ
ለባት ፡ ምድር ፡ እስክፈልሳችሁ ፡ ድረስ ፡ በሕ
ይወት ፡ እንድትኖሩ ፡ እንዳትሞቱም ፡ ነው ።
ሕዝቅያስም ፡— እግዚአብሔር ፡ ያድነናል ፡
፴፫ ብሎ ፡ ቢያታልላችሁ ፡ አትስሙት ። በውኑ ፡
የአሕዛብ ፡ አማልክት ፡ አገሮቻቸውን ፡ ከአሦር ፡
፴፬ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ አድነዋቸዋልን ? የሐማትና ፡
የአርፋድ ፡ አማልክት ፡ ወዴት ፡ አሉ ? የሴፈር
ዋይምና ፡ የሄና ፡ የዒዋም ፡ አማልክት ፡ ወዴት ፡
፴፭ አሉ ? ሰማርያን ፡ ከእጄ ፡ አድነዋታልን ? እግ
ዚአብሔር ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ከእጄ ፡ ያድን ፡
ዘንድ ፡ ከአገሮቹ ፡ አማልክት ፡ ሁሉ ፡ አገሩን ፡
ከእጄ ፡ ያዳነ ፡ ማን ፡ ነው ?
፴፮ ሕዝቡም ፡ ዝም ፡ አሉ ÷ አንዳችም ፡ አልመ
ለሱለትም ፤ ንጉሡ ፡ እንዳይመልሱለት ፡ አዝዞ ፡
፴፯ ነበርና ። የቤቱ ፡ አዛዥ ፡ የኬልቅያስ ፡ ልጅ ፡
ኤልያቄም ፡ ጸሐፊውም ፡ ሳምናስ ፡ ታሪክ ፡ ጸሐ
ፊም ፡ የአሳፍ ፡ ልጅ ፡ ዮአስ ፡ ልብሳቸውን ፡ ቀድ
ደው ፡ ወደ ፡ ሕዝቅያስ ፡ መጡ ÷ የራፋስቂስ
ንም ፡ ቃል ፡ ነገሩት ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ ንጉሡም ፡ ሕዝቅያስ ፡ ይህን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡
ልብሱን ፡ ቀደደ ÷ ማቅም ፡ ለበሰ ÷ ወደ ፡ እግዚ
፪ አብሔርም ፡ ቤት ፡ ገባ ። የቤቱንም ፡ አዛዥ ፡
ኤልያቄምን ፡ ጸሐፊውንም ፡ ሳምናስን ፡ የካህና
ቱንም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ማቅ ፡ ለብሰው ፡ ወደ ፡
ነቢዩ ፡ ወደ ፡ አሞጽ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢሳይያስ ፡
፫ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ላካቸው ። እነርሱም ፡— ሕዝ
ቅያስ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ይህ ፡ ቀን ፡ የመከ
ራና ፡ የተግሣጽ ፡ የዘለፋም ፡ ቀን ፡ ነው ፤ ልጆች ፡
የሚወለዱበት ፡ ጊዜ ፡ ደርሶአል ÷ ለመውለ
፬ ድም ፡ ኃይል ፡ የለም ። ምናልባት ፡ በሕያው ፡
አምላክ ፡ ላይ ፡ ይገዳደር ፡ ዘንድ ፡ ጌታው ፡ የአ
ሦር ፡ ንጉሥ ፡ የላከውን ፡ የራፋስቂስን ፡ ቃል ፡
ሁሉ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይሰማ ፡ እንደ ፡
ሆነ ÷ አምላክህ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ስለ ፡ ሰማው ፡
ቃል ፡ ይገሥጸው ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ ስለዚህ ፡ ለቀ
፭ ረው ፡ ቅሬታ ፡ ጸልይ ፡ አሉት ። እንዲሁ ፡ የን
ጉሡ ፡ የሕዝቅያስ ፡ ባሪያዎች ፡ ወደ ፡ ኢሳይ
፮ ያስ ፡ መጡ ። ኢሳይያስም ፡— ለጌታችሁ ፡—
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የአሦር ፡
ንጉሥ ፡ ባሪያዎች ፡ ስለ ፡ ሰደቡኝ ÷ ስለ ፡ ሰማ
፯ ኸው ፡ ቃል ፡ አትፍራ ። እነሆ ÷ በላዩ ፡ መን
ፈስን ፡ እሰድዳለሁ ÷ ወሬንም ፡ ይሰማል ÷ ወደ ፡
ምድሩም ፡ ይመለሳል ፤ በምድሩም ፡ በሰይፍ ፡
እንዲወድቅ ፡ አደርገዋለሁ ፡ በሉት ፡ አላቸው ።
፰ የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ ከለኪሶ ፡ እንደ ፡ ራቀ ፡
ሰምቶ ፡ ነበርና ፡ ራፋስቂስ ፡ ተመልሶ ፡ በልብና ፡
ሲዋጋ ፡ አገኘው ። እርሱም ፡— የኢትዮጵያ ፡ ፱
ንጉሥ ፡ ቲርሐቅ ፡ ሊወጋህ ፡ መጥቶአል ፡ የሚል ፡
ወሬ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ ሕዝቅያስ ፡
መልእክተኞችን ፡ ላከ ÷ እንዲህ ፡ ሲል ፡— ለይ ፲
ሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ለሕዝቅያስ ፡ እንዲህ ፡ ብላችሁ ፡
ንገሩት ፡— ኢየሩሳሌም ፡ በአሦር ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡
አትሰጥም ፡ ብሎ ፡ የምትታመንበት ፡ አምላክህ ፡
አያታልልህ ። እነሆ ÷ የአሦር ፡ ነገሥታት ፡ በም ፲፩
ድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያደረጉትን ÷ እንዴትስ ፡ እን
ዳጠፉአቸው ፡ ሰምተሃል ፤ አንተስ ፡ ትድና
ለህን ? አባቶቼ ፡ ያጠፉአቸውን ÷ ጎዛንን ÷ ፲፪
ካራንን ÷ ራፌስን ÷ በተላሳር ፡ የነበሩትንም ፡
የዔድንን ፡ ልጆች ÷ የአሕዛብ ፡ አማልክት ፡
አዳኑአቸውን ? የሐማት ፡ ንጉሥ ÷ የአርፋድ ፡ ፲፫
ንጉሥ ÷ የሴፈርዋይም ፡ ከተማ ፡ ንጉሥ ÷ የሄ
ናና ፡ የዒዋ ፡ ንጉሥ ፡ ወዴት ፡ አሉ ?
ሕዝቅያስም ፡ ደብዳቤውን ፡ ከመልእክተ ፲፬
ኞች ፡ እጅ ፡ ተቀብሎ ፡ አነበበው ፤ ሕዝቅያስም ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ወጥቶ ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ፊት ፡ ዘረጋው ። ሕዝቅያስም ፡ ወደ ፡ ፲፭
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ጸለየ ፡— በኪ
ሩቤል ፡ ላይ ፡ የምትቀመጥ ፡ የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ አቤቱ ÷ አንተ ፡ ብቻህን ፡ የምድር ፡ ነገሥ
ታት ፡ ሁሉ ፡ አምላክ ፡ ነህ ፤ ሰማይንና ፡ ምድ
ርን ፡ ፈጥረሃል ። አቤቱ ÷ ጆሮህን ፡ አዘንብ ፲፮
ልና ፡ ስማ ፤ አቤቱ ÷ ዓይንህን ፡ ክፈትና ፡ እይ ፤
በሕያው ፡ አምላክ ፡ ላይ ፡ ይገዳደር ፡ ዘንድ ፡
የላከውን ፡ የሰናክሬምን ፡ ቃል ፡ ስማ ። አቤቱ ÷ ፲፯
በእውነት ፡ የአሦር ፡ ነገሥታት ፡ አሕዛብንና ፡
ምድራቸውን ፡ አፍርሰዋል ÷ አማልክቶቻቸ ፲፰
ውንም ፡ በእሳት ፡ ላይ ፡ ጥለዋል ፤ የእንጨ
ትና ፡ የድንጋይ ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ ሥራ ፡ ነበሩ ፡
እንጂ ፡ አማልክት ፡ አልነበሩምና ፤ ስለዚህ ፡
አጥፍተዋቸዋል ። እንግዲህም ፡ አምላካችን ፡ ፲፱
አቤቱ ÷ የምድር ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡
ብቻ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡
ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ ከእጁ ፡ እንድታድነን ፡ እለም
ንሃለሁ ።
የአሞጽም ፡ ልጅ ፡ ኢሳይያስ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ፳
ወደ ፡ ሕዝቅያስ ፡ ላከ ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ስለ ፡ አሦር ፡
ንጉሥ ፡ ስለ ፡ ሰናክሬም ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ የለመንኸ
ውን ፡ ሰምቻለሁ ። እግዚአብሔር ፡ በእርሱ ፡ ፳፩
ላይ ፡ የተናገረው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ፡— ድን
ግሊቱ ፡ የጽዮን ፡ ልጅ ፡ ቀላል ፡ አድርጋሃለች ÷
በንቀትም ፡ ስቃብሃለች ፤ የኢየሩሳሌም ፡ ልጅ ፡
በላይህ ፡ ራስዋን ፡ ነቅንቃብሃለች ። የተገዳደ ፳፪
ርኸው ÷ የሰደብኸውስ ፡ ማን ፡ ነው ? ቃልህንስ ፡
ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደረግኸው ፡ ዓይንህንም ፡ ወደ ፡
ላይ ፡ ያነሣኸው ፡ በማን ፡ ላይ ፡ ነው ? በእስራ
ኤል ፡ ቅዱስ ፡ ላይ ፡ ነው ። አንተስ ፡— በሰረ ፳፫
ገላዬ ፡ ብዛት ፡ ወደ ፡ ተራሮች ፡ ከፍታ ÷ ወደ ፡
ሊባኖስ ፡ ጥግ ፡ ላይ ፡ ወጥቻለሁ ፤ ረጃጅሞቹንም ፡
ዝግባዎች ፡ የተመረጡትንም ፡ ጥዶች ፡ እቈር

ጣለሁ ፥ ወደ ፡ አገሩም ፡ ዳርቻና ፡ ወደ ፡ ቀርሚ
፳፬ ሎስ ፡ ዱር ፡ እገባለሁ ። ቈፈርሁም ፥ እንግዳ
ውኃም ፡ ውኃ ፡ ጠጣሁ ፤ የተገደበውንም ፡
ውኃ ፡ ሁሉ ፡ በእግሬ ፡ ጫማ ፡ አደርቃለሁ ፡
ብለህ ፡ በመልእክተኞችህ ፡ እጅ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ላይ ፡ ተገዳደርህ ።

፳፭ እኔ ፡ ጥንቱን ፡ እንደ ፡ ሠራሁት ፥ ቀድሞ
ውንም ፡ እንዳደረግሁት ፡ አልሰማህምን ? አሁ
ንም ፡ የተመሸጉትን ፡ ከተሞች ፡ የፍርስራሽ ፡
ክምር ፡ እስኪሆኑ ፡ ድረስ ፡ እንድታፈርስ ፡ አደረ
፳፮ ግሁህ ። ስለዚህም ፡ የሚኖሩባቸው ፡ ሰዎች ፡
እጃቸው ፡ ዝሎአል ፥ ደንግጠውም ፡ ታውከ
ዋል ፤ እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሣር ፥ እንደ ፡ ለም
ለምም ፡ ቡቃያ ፥ በሰገነትም ፡ ላይ ፡ እንዳለ ፡
ሣር ፥ ሳይሸት ፡ ዋግ ፡ እንደ ፡ መታውም ፡ እህል ፡
፳፯ ሆነዋል ። እኔ ፡ ግን ፡ መቀመጫህንና ፡ መው
ጫህንም ፡ መግቢያህንም ፥ በእኔም ፡ ላይ ፡ የተ
፳፰ ቈጣኸውን ፡ ቍጣ ፡ አውቄአለሁ ። ቍጣህና ፡
ትዕቢትህ ፡ ወደ ፡ ጆሮዬ ፡ ደርሶአልና ፡ ስለዚህ ፡
ስናጋዬን ፡ በአፍንጫህ ፥ ልጓሜንም ፡ በከንፈ
ርህ ፡ አደርጋለሁ ፥ በመጣህበትም ፡ መንገድ ፡
እመልስሃለሁ ።

፳፱ ይህም ፡ ምልክት ፡ ይሆንሃል ፤ በዚህ ፡ ዓመት ፡
የገበውን ፥ በሁለተኛውም ፡ ዓመት ፡ ከገበው ፡
የበቀለውን ፡ ትበላላችሁ ፤ በሦስተኛውም ፡
ዓመት ፡ ትዘራላችሁ ፥ ታጭዱማላችሁ ፥ ወይን
ንም ፡ ትተክላላችሁ ፥ ፍሬውንም ፡ ትበላላችሁ ።
፴ ያመለጠው ፡ የይሁዳ ፡ ቤት ፡ ቅሬታ ፡ ሥሩን ፡
ወደ ፡ ታች ፡ ይሰድዳል ፥ ወደ ፡ ላይም ፡ ያፈ
፴፩ ራል ። ከኢየሩሳሌም ፡ ቅሬታ ፡ ከጽዮንም ፡
ትራፊ ፡ ያመለጡት ፡ ይወጣሉና ፤ የሠራዊት ፡
ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቅንዓት ፡ ይህን ፡ ያደር
፴፪ ጋል ። ስለዚህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ አሦር ፡
ንጉሥ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ወደዚች ፡ ከተማ ፡
አይመጣም ፥ ፍላጻንም ፡ አይወረውርባትም ፥
በጋሻም ፡ አይመጣባትም ፥ የአፈርንም ፡ ድል
፴፫ ድል ፡ አይደለድልባትም ። በመጣበት ፡ መን
ገድ ፡ በዚያው ፡ ይመለሳል ፥ ወደዚህችም ፡
ከተማ ፡ አይመጣም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
፴፬ ስለ ፡ እኔም ፥ ስለ ፡ ባሪያዬም ፡ ስለ ፡ ዳዊት ፡
ይህችን ፡ ከተማ ፡ አድናት ፡ ዘንድ ፡ እጋርዳታ
ለሁ ።

፴፭ በዚያችም ፡ ሌሊት ፡ የእግዚአብሔር ፡
መልአክ ፡ ወጣ ፥ ከአሦራውያንም ፡ ሰፈር ፡
መቶ ፡ ሰማንያ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ገደለ ፤ ማለ
ዳም ፡ በተነሡ ፡ ጊዜ ፥ እነሆ ፥ ሁሉ ፡ በድኖች ፡
፴፮ ነበሩ ። የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ ሰናክሬም ፡ ተነ
ሥቶ ፡ ሄደ ፥ ተመልሶም ፡ በነነዌ ፡ ተቀመጠ ።
፴፯ በአምላኩም ፡ በናሳራክ ፡ ቤት ፡ ሲሰግድ ፡
ልጆቹ ፡ አድራሜሌክና ፡ ሳራሳር ፡ በሰይፍ ፡ ገደ
ሉት ፤ ወደ ፡ አራራትም ፡ አገር ፡ ኰበለሉ ።
ልጁም ፡ አስራዶን ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ በዚያም ፡ ወራት ፡ ሕዝቅያስ ፡ እስከ ፡ ሞት ፡
ድረስ ፡ ታመመ ። ነቢዩም ፡ የአሞጽ ፡ ልጅ ፡ ኢሳ
ይያስ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጥቶ ፡— እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— ትሞታለህ ፡ እንጂ ፡ በሕይ
ወት ፡ አትኖርምና ፡ ቤትህን ፡ አስተካክል ፡
አለው ። ፪ ፊቱንም ፡ ወደ ፡ ግድግዳው ፡ መልሶ ፡
እንዲህ ፡ ሲል ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸለየ ፡—
፫ አቤቱ ፥ በፊትህ ፡ በእውነትና ፡ በፍጹም ፡ ልብ ፡
እንደ ፡ ሄድሁ ፥ ደስ ፡ የሚያሰኝህንም ፡ እን
ዳደረግሁ ፡ ታስብ ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ። ሕዝ
ቅያስም ፡ እጅግ ፡ አድርጎ ፡ አለቀሰ ። ፬ ኢሳይያ
ስም ፡ ወደ ፡ መካከለኛው ፡ ከተማ ፡ አደባባይ ፡
ሳይደርስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንዲህ ፡
ሲል ፡ መጣለት ፡— ፭ ተመልሰህ ፡ የሕዝቤን ፡
አለቃ ፡ ሕዝቅያስን ፡ እንዲህ ፡ በለው ፡— የአባ
ትህ ፡ የዳዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፡— ጸሎትህን ፡ ሰምቻለሁ ፥ እን
ባህንም ፡ አይቻለሁ ፤ እነሆ ፥ እፈውስሃለሁ ፤
በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ ትወጣለህ ። ፮ በዕድሜህም ፡ ላይ ፡ አሥራ ፡
አምስት ፡ ዓመት ፡ እጨምራለሁ ፤ አንተንና ፡
ይህችን ፡ ከተማ ፡ ከአሦር ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ እታ
ደጋለሁ ፤ ስለ ፡ እኔም ፡ ስለ ፡ ባሪያዬም ፡ ስለ ፡
ዳዊት ፡ ይህችን ፡ ከተማ ፡ እጋርዳታለሁ ። ፯ ኢሳ
ይያስም ፡— የበለስ ፡ ጥፍጥፍ ፡ አምጡልኝ ፡
አለ ፤ አምጥተውም ፡ በእባጩ ፡ ላይ ፡ አደረጉ
ለት ፥ እርሱም ፡ ተፈወሰ ።

፰ ሕዝቅያስም ፡ ኢሳይያስን ፡— እግዚአብሔር ፡
እንዲፈውሰኝ ፥ እኔስ ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እንድወጣ ፡ ምልክቱ ፡
ምንድር ፡ ነው ? አለው ። ፱ ኢሳይያስም ፡— እግ
ዚአብሔር ፡ የተናገረውን ፡ ነገር ፡ እንዲፈጽ
መው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ምልክቱ ፡
ይህ ፡ ይሆንልሃል ፤ ጥላው ፡ አሥር ፡ ደረጃ ፡
ወደ ፡ ፊት ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ ወይም ፡ አሥር ፡
ደረጃ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ይመለስ ፡ ዘንድ ፡ ትወድዳ
ለህን ? አለ ። ፲ ሕዝቅያስም ፡— ጥላው ፡ አሥር ፡
ደረጃ ፡ ቢጨምር ፡ ቀላል ፡ ነገር ፡ ነው ፤ እንዲህ ፡
አይሁን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ጥላው ፡ አሥር ፡ ደረጃ ፡
ወደ ፡ ኋላ ፡ ይመለስ ፡ አለው ። ፲፩ ነቢዩም ፡ ኢሳ
ይያስ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኸ ፤ ጥላው
ንም ፡ በአካዝ ፡ የጥላ ፡ ስፍራ ፡ ሰዓት ፡ ላይ ፡ በወ
ረደበት ፡ መንገድ ፡ አሥር ፡ ደረጃ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡
መለሰው ።

፲፪ በዚያም ፡ ወራት ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ የባል
ዳን ፡ ልጅ ፡ መሮዳክ ፡ ባልዳን ፡ ሕዝቅያስ ፡ እንደ ፡
ታመመ ፡ ሰምቶ ፡ ነበርና ፡ ደብዳቤና ፡ እጅ ፡
መንሻ ፡ ወደ ፡ ሕዝቅያስ ፡ ላከ ። ፲፫ ሕዝቅያስም ፡
ደስ ፡ አለው ፥ ግምጃ ፡ ቤቱንም ፡ ሁሉ ፥ ብሩ
ንና ፡ ወርቁንም ፥ ቅመሙንና ፡ የከበረውንም ፡

ዘይት ፥ መሣሪያም ፡ ያለበትን ፡ ቤት ፥ በቤተ ፡
መዛግብቱም ፡ የተገኘውን ፡ ሁሉ ፡ አሳያቸው ፤
በቤቱና ፡ በግዛቱ ፡ ሁሉ ፡ ከለው ፡ ሕዝቅያስ ፡
፲፭ ያላሳያቸው ፡ የለም ። ነቢዩም ፡ ኢሳይያስ ፡
ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ሕዝቅያስ ፡ መጥቶ ፡—
እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ምን ፡ አሉ ? ከወዴትስ ፡
መጡልህ ? አለው ። ሕዝቅያስም ፡— ከሩቅ ፡
፲፮ አገር ፡ ከባቢሎን ፡ መጡ ፡ አለው ። እርሱም ፡—
በቤትህ ፡ ያዩት ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለው ፤ ሕዝ
ቅያስም ፡— በቤቴ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ አይተዋል ፤
በቤተ ፡ መዛግብቴ ፡ ከለው ፡ ያላሳየኋቸው ፡
የለም ፡ አለው ።

፲፯ ኢሳይያስም ፡ ሕዝቅያስን ፡— የእግዚአብሔ
፲፰ ርን ፡ ቃል ፡ ስማ ። እነሆ ፥ በቤትህ ፡ ያለው ፡
ሁሉ ፥ አባቶችህም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ያከ
ማቹት ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ የሚፈልስበት ፡
ወራት ፡ ይመጣል ፤ ምንም ፡ አይቀርም ፥ ይላል ፡
፲፱ እግዚአብሔር ። ከአንተም ፡ ከሚወጡት ፡ ከም
ትወልዳቸው ፡ ልጆችህ ፡ ማርከው ፡ ይወስዳሉ ፤
በባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ጃንደረ
፳ ቦች ፡ ይሆናሉ ፡ አለው ። ሕዝቅያስም ፡ ኢሳይያ
ስን ፡— የተናገርኸው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡
መልካም ፡ ነው ፡ አለው ። ደግሞም ፡— በዘ
መኔ ፡ ሰላምና ፡ እውነት ፡ የሆነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
፳፩ መልካም ፡ አይደለምን ? አለ ። የቀረውም ፡
የሕዝቅያስ ፡ ነገር ፥ ጭከናውም ፡ ሁሉ ፥ ኵሬ
ውንና ፡ መስኖውንም ፡ እንደ ፡ ሠራ ፥ ውኃው
ንም ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ እንዳመጣ ፥ በይሁዳ ፡
ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደ
፳፩ ለምን ? ሕዝቅያስም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀ
ላፋ ፤ ልጁም ፡ ምናሴ ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ ምናሴም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የአ
ሥራ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፤ በኢየሩሳ
ሌምም ፡ አምሳ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ የእ
፪ ናቱ ፡ ስም ፡ ሐፍሴባ ፡ ነበረ ። እግዚአብሔርም ፡
ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ እንዳወጣቸው ፡
እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ርኵሰት ፡ በእግዚአብሔር ፡
፫ ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረገ ። አባቱም ፡ ሕዝቅ
ያስ ፡ ያፈረሳቸውን ፡ የኮረብታውን ፡ መስገጃ
ዎች ፡ መልሶ ፡ ሠራ ፤ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡
አክዓብ ፡ እንዳደረገው ፡ ለበኣል ፡ መሠዊያ ፡
ሠራ ፥ የማምለኪያ ፡ ዐፀድንም ፡ ተከለ ፥ ለሰ
ማይም ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ ሰገደ ፡ አመለካቸ
፬ ውም ። እግዚአብሔርም ፡— ስሜን ፡ በኢየሩ
ሳሌም ፡ አኖራለሁ ፡ ባለው ፡ በእግዚአብሔር ፡
፭ ቤት ፡ መሠዊያዎችን ፡ ሠራ ። በእግዚአብሔ
ርም ፡ ቤት ፡ በሁለቱ ፡ ወለሎች ፡ ላይ ፡ ለሰማይ ፡
፮ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ መሠዊያዎችን ፡ ሠራ ። ልጁ
ንም ፡ በእሳት ፡ አሳለፈ ፥ ሞራ ፡ ገላጭም ፡ ሆነ ፥
አስማትም ፡ አደረገ ፥ መናፍስት ፡ ጠሪዎችንና ፡
ጠንቋዮችንም ፡ ሰበሰበ ፤ ያስቈጣውም ፡ ዘንድ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እጅግ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደ

፯ ረገ ። እግዚአብሔርም ፡ ለዳዊትና ፡ ለልጁ ፡ ለሰ
ሎሞን ፡— በዚህ ፡ ቤት ፡ ከእስራኤልም ፡ ነገድ ፡
ሁሉ ፡ በመረጥኋት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ስሜን ፡
፰ ለዘላለም ፡ አኖራለሁ ፤ ያዘዝኋቸውንም ፡ ሁሉ ፥
ባሪያዬም ፡ ሙሴ ፡ ያዘዛቸውን ፡ ሕግ ፡ ሁሉ ፡
ቢያደርጉ ፡ ቢጠብቁም ፡ ለአባቶቻቸው ፡ ከሰ
ጠኋት ፡ ምድር ፡ የእስራኤልን ፡ እግር ፡ እንደ ፡
ገና ፡ አላቅበዘብዝም ፡ ባለው ፡ ቤት ፡ የሠራ
ውን ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀድን ፡ የተቀረጸውን ፡
፱ ምስል ፡ አቆመ ። ነገር ፡ ግን ፡ አልሰሙም ፤ እግ
ዚአብሔርም ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡
ካጠፋቸው ፡ ከአሕዛብ ፡ ይልቅ ፡ ክፉ ፡ ይሠሩ ፡
ዘንድ ፡ ምናሴ ፡ አሳታቸው ።

፲ እግዚአብሔርም ፡ በባሪያዎቹ ፡ በነቢያት ፡
፲፩ እጅ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ተናገረ ፡— የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡
ምናሴ ፡ ይህን ፡ ርኵሰት ፡ አድርጎአልና ፥ ከፊ
ቱም ፡ የነበሩ ፡ አሞራውያን ፡ ከሠሩት ፡ ሁሉ ፡
ይልቅ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ሠርቶአልና ፥ ይሁዳንም ፡
፲፪ ደግሞ ፡ በጣዖታቱ ፡ አስቶአልና ፡ ስለዚህ ፡ የእ
ስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እነሆ ፥ የሚሰማውን ፡ ሁሉ ፡ ሁለቱ ፡
ጆሮቹ ፡ ጭው ፡ የሚያደርግ ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ በኢየ
፲፫ ሩሳሌምና ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ አመጣለሁ ። የሰማር
ያንም ፡ ገመድ ፡ የአክዓብንም ፡ ቤት ፡ ቱንቢ ፡ በኢ
የሩሳሌም ፡ ላይ ፡ እዘረጋለሁ ፤ ሰውም ፡ ወጭ
ቱን ፡ እንዲወለውል ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ወልውዬ ፡
፲፬ እገለብጣታለሁ ። የርስቴንም ፡ ቅሬታ ፡ እጥላ
ለሁ ፥ በጠላቶቻቸውም ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣቸ
ዋለሁ ፥ ለጠላቶቻቸውም ፡ ሁሉ ፡ ምርኮና ፡ ብዝ
፲፭ በዛ ፡ ይሆናሉ ፤ አባቶቻቸው ፡ ከግብጽ ፡ ከወጡ ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በፊቴ ፡ ክፉ ፡ ሠር
ተዋልና ፥ አስቈጥተውኛልና ።

፲፮ ደግሞም ፡ ምናሴ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ክፉ ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ይሁዳን ፡ ካሳተበት ፡ ኃጢ
አት ፡ ሌላ ፡ ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ ኢየሩሳሌምን ፡
እስኪሞላት ፡ ድረስ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ንጹሕ ፡
፲፯ ደም ፡ አፈሰሰ ። የምናሴም ፡ የቀረው ፡ ነገርና ፡
የሠራው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፥ ያደረገውም ፡ ኃጢ
አት ፥ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡
፲፰ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ምናሴም ፡ ከአባቶቹ ፡
ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በቤቱም ፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡
በዖዛ ፡ አትክልት ፡ ተቀበረ ፤ ልጁም ፡ አሞጽ ፡
በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

፲፱ አሞጽም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡
ሁለት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፤ በኢየሩሳሌ
ምም ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡ የዮ
ጥባ ፡ ሰው ፡ የሐሩስ ፡ ልጅ ፡ ሜሶላም ፡ ነበረች ።
፳ አባቱም ፡ ምናሴ ፡ እንዳደረገ ፡ በእግዚአብሔር ፡
፳፩ ፊት ፡ ክፉ ፡ ሠራ ። አባቱም ፡ በሄደበት ፡ መን
ገድ ፡ ሁሉ ፡ ሄደ ፥ አባቱም ፡ ያመለካቸውን ፡
፳፪ ጣዖታት ፡ አመለከ ፡ ሰገደላቸውም ። የአባቶ
ቹንም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተወ ፥ በእ
፳፫ ግዚአብሔርም ፡ መንገድ ፡ አልሄደም ። የአሞ
ጽም ፡ ባሪያዎች ፡ አሴሩበት ፡ ንጉሡንም ፡ በቤቱ ፡

፳፬ ውስጥ ፡ ገደሉት ፥ የአገሩ ፡ ሕዝብ ፡ ግን ፡ በን
ጉሡ ፡ በአሞጽ ፡ ላይ ፡ ያሴሩበትን ፡ ሁሉ ፡ ገደሉ ፤
የአገሩም ፡ ሕዝብ ፡ ልጁን ፡ ኢዮስያስን ፡ በእ
፳፭ ርሱ ፡ ፋንታ ፡ አነገሡት ። የአሞጽም ፡ የቀረው ፡
ነገርና ፡ የሠራው ፡ ሥራ ፥ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡
፳፮ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? በዖ
ዛም ፡ አትክልት ፡ በለው ፡ በመቃብሩ ፡ ተቀበረ ፤
ልጁም ፡ ኢዮስያስ ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ ኢዮስያስም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የስ
ምንት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡
ሠላሳ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡ ከበ
ሱሮት ፡ የሆነ ፡ የአዳያ ፡ ልጅ ፡ ይዲዳ ፡ ነበረች ።
፪ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገርን ፡ አደ
ረገ ፥ በአባቱም ፡ በዳዊት ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡
ሄደ ፥ ቀኝም ፡ ግራም ፡ አላለም ።
፫ በንጉሡም ፡ በኢዮስያስ ፡ በአሥራ ፡ ስምን
ተኛው ፡ ዓመት ፡ በስምንተኛው ፡ ወር ፡ ንጉሡ ፡
ጸሐፊውን ፡ የሜሱላምን ፡ ልጅ ፡ የኤዜልያስን ፡
ልጅ ፡ ሳፋንን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
፬ ላከው ፥ እንዲህም ፡ አለው ፦ የመቅደሱ ፡
በረኞች ፡ ከሕዝቡ ፡ የሰበሰቡትን ፡ ወደ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ቤት ፡ የገባውን ፡ ገንዘብ ፡ ይደምር ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ ካህናቱ ፡ አለቃ ፡ ወደ ፡ ኬልቅያስ ፡
፭ ሂድ ። በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ላሉት ፡ ሠራ
ተኞች ፡ አለቆች ፡ ይስጡት ፤ እነርሱም ፡ የተ
ናደውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ለሚጠግ
፮ ኑት ፡ ሠራተኞች ፥ ለአናጢዎችና ፡ ለጠራቢ
ዎች ፥ ለድንጋይም ፡ ወቃሪዎች ፥ መቅደሱ
ንም ፡ ለመጠገን ፡ እንጨትንና ፡ የተወቀረውን ፡
፯ ድንጋይ ፡ ለሚገዙ ፡ ይክፈሉት ። ነገር ፡ ግን ፡
እነርሱ ፡ የታመኑ ፡ ነበሩና ፡ በእጃቸው ፡ ስለ ፡
ተሰጠ ፡ አይቈጣጠሩአቸውም ፡ ነበር ።
፰ ካህኑም ፡ ኬልቅያስ ፡ ጸሐፊውን ፡ ሳፋንን ፦
የሕጉን ፡ መጽሐፍ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
አገኘሁ ፡ አለው ፤ ኬልቅያስም ፡ መጽሐፉን ፡
ለሳፋን ፡ ሰጠው ፥ እርሱም ፡ አነበበው ።
፱ ጸሐፊውም ፡ ሳፋን ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ መጣ ፥
ለንጉሡም ፦ በመቅደሱ ፡ የተገኘውን ፡ ገንዘብ ፡
በሪያዎችህ ፡ አፈሰሱት ፥ በእግዚአብሔርም ፡
ቤት ፡ ሠራተኞች ፡ ላይ ፡ ለተሾሙት ፡ አለቆች ፡
፲ ሰጡት ፡ ብሎ ፡ አወራለት ። ጸሐፊውም ፡
ሳፋን ፡ ለንጉሡ ፦ ካህኑ ፡ ኬልቅያስ ፡ መጽ
ሐፍ ፡ ሰጥቶኛል ፡ ብሎ ፡ ነገረው ። ሳፋንም ፡
፲፩ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ አነበበው ። ንጉሡም ፡ የሕጉን ፡
መጽሐፍ ፡ ቃል ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ልብሱን ፡ ቀደደ ።
፲፪ ንጉሡም ፡ ካህኑን ፡ ኬልቅያስን ፥ የሳፋንንም ፡
ልጅ ፡ አኪቃምን ፥ የሚክያስንም ፡ ልጅ ፡ ዓክ
ቦርን ፥ ጸሐፊውንም ፡ ሳፋንን ፥ የንጉሡንም ፡
፲፫ ብላቴና ፡ ዓሳያን ፦ አባቶቻችን ፡ በእርስዋ ፡
የተጻፈውን ፡ ሁሉ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ የዚህችን ፡
መጽሐፍ ፡ ቃል ፡ ስላልሰሙ ፡ በላያችን ፡ የነ
ደደ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ እጅግ ፡ ነውና ፡
ሂዱችሁ ፡ ስለ ፡ እኔና ፡ ስለ ፡ ሕዝቡ ፡ ስለ ፡ ይሁ
ዳም ፡ ሁሉ ፡ የዚህችን ፡ የተገኘችውን ፡ መጽ
ሐፍ ፡ ቃል ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠይቁ ፡ ብሎ ፡
አዘዛቸው ።
፲፬ እንዲሁም ፡ ካህኑ ፡ ኬልቅያስና ፡ አኪቃም ፡
ዓክቦርም ፡ ሳፋንና ፡ ዓሳያም ፡ ወደ ፡ ልብስ ፡
ጠባቂው ፡ ወደ ፡ ሐስራ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ቲቁዋ ፡
ልጅ ፡ ወደ ፡ ሴሌም ፡ ሚስት ፡ ወደ ፡ ነቢይቱ ፡
ወደ ፡ ሕልዳና ፡ ሄዱ ፤ እርስዋም ፡ በኢየሩሳሌም ፡
በሁለተኛው ፡ ክፍል ፡ ተቀምጣ ፡ ነበር ፤ ከእር
፲፭ ስዋም ፡ ጋር ፡ ተነጋገሩ ። እርስዋም ፡ አለቻ
ቸው ፦ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፦ ወደ ፡ እኔ ፡ ለላከችሁ ፡ ሰው ፡
፲፮ እንዲህ ፡ ብላችሁ ፡ ንገሩት ፦ እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፦ እነሆ ፥ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡
እንዳነበበው ፡ እንደ ፡ መጽሐፉ ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡
በዚህ ፡ ስፍራና ፡ በሚኖሩበት ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡
፲፯ ነገር ፡ አመጣለሁ ። በእጃቸው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡
ያስቈጡኝ ፡ ዘንድ ፡ ትተውኛልና ፥ ለሌሎችም ፡
አማልክት ፡ ዐጥነዋልና ፡ ቍጣዬ ፡ በዚህ ፡ ስፍራ ፡
፲፰ ላይ ፡ ይነድዳል ፥ አይጠፋምም ። እግዚአብ
ሔርን ፡ ለመጠየቅ ፡ ለላከችሁ ፡ ለይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡
ግን ፡ እንዲህ ፡ በሉት ፦ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ስለ ፡ ሰማ
፲፱ ኸው ፡ ቃል ፥ ልብህ ፡ ገር ፡ ሆኖአልና ፥ እነር
ሱም ፡ ለድንቅና ፡ ለመርገም ፡ እንዲሆኑ ፡ በዚህ ፡
ስፍራና ፡ በሚኖሩበት ፡ ላይ ፡ የተናገርሁትን ፡
ሰምተህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ተዋርደሃልና ፥
ልብስህን ፡ ቀድደሃልና ፥ በፊቴም ፡ አልቅሰሃ
ልና ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ ሰምቼሃለሁ ፡ ይላል ፡ እግዚአብ
፳ ሔር ። ስለዚህም ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ አባቶችህ ፡
እሰበስብሃለሁ ፥ በሰላምም ፡ ወደ ፡ መቃብርህ ፡
ትሰበሰባለህ ፤ በዚህም ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ የማመ
ጣውን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ዓይኖችህ ፡ አያዩም ።
ይህንም ፡ ለንጉሡ ፡ አወሩለት ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ ንጉሡም ፡ ላከ ፤ የይሁዳንና ፡ የኢየሩሳሌም
፪ ንም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰባቸው ። ንጉ
ሡም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ወጣ ፤ ከእ
ርሱም ፡ ጋር ፡ የይሁዳ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፥ በኢየሩ
ሳሌምም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፥ ካህናቱና ፡ ነቢያ
ቱም ፥ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ከታናሾቹ ፡ ጀምሮ ፡
እስከ ፡ ታላቆቹ ፡ ድረስ ፡ ወጡ ፤ በእግዚአብ
ሔርም ፡ ቤት ፡ የተገኘውን ፡ የቃል ፡ ኪዳኑን ፡
መጽሐፍ ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ በጆሮአቸው ፡ አነበበ ።
፫ ንጉሡም ፡ በዓምደ ፡ ወርቁ ፡ አጠገብ ፡ ቆሞ ፡
እግዚአብሔርን ፡ ተከትሎ ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፥
ትእዛዙንና ፡ ምስክሩንም ፡ ሥርዓቱንም ፡ በፍ
ጹም ፡ ልቡና ፡ በፍጹም ፡ ነፍሱ ፡ ይጠብቅ ፡
ዘንድ ፥ በዚሁም ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈውን ፡
የቃል ፡ ኪዳን ፡ ቃል ፡ ያጸና ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ፊት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረገ ፤ ሕዝቡም ፡
ሁሉ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ገቡ ።

፬፤ ንጉሡም ፡ የካህናቱን ፡ አለቃ ፡ ኬልቅያስን ፡
በሁለተኛውም ፡ መዓርግ ፡ ያሉትን ፡ ካህናትን ፡
በረኞቹንም ፡ ለበአልና ፡ ለማምለኪያ ፡ ዐፀድ ፡
ለሰማይም ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ የተሠሩትን ፡ ዕቃ
ዎች ፡ ሁሉ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ ያወጡ ፡
ዘንድ ፡ አዘዛቸው ፤ ከኢየሩሳሌምም ፡ ውጭ ፡
በቄድሮን ፡ ሜዳ ፡ አቃጠላቸው ፥ አመዱንም ፡
፭፤ ወደ ፡ ቤቴል ፡ ወሰደው ። የይሁዳ ፡ ነገሥታ
ትም ፡ በይሁዳ ፡ ከተሞች ፡ በነበሩት ፡ በኮረብ
ታው ፡ መስገጃዎች ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ ዙሪያ ፡
ባሉ ፡ መስገጃዎች ፡ ያጥኑ ፡ ዘንድ ፡ ያኖሩአቸ
ውን ፡ የጣዖቱን ፡ ካህናት ፥ ለበአልና ፡ ለፀሐይ ፡
ለጨረቃና ፡ ለከዋክብት ፡ ለሰማይም ፡ ሠራዊት ፡
፮፤ ሁሉ ፡ ያጥኑ ፡ የነበሩትንም ፡ አስወገደ ። የማም
ለኪያ ፡ ዐፀድንም ፡ ጣዖት ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ውጭ ፡ ወደ ፡ ቄድ
ሮን ፡ ፈፋ ፡ አወጣው ፤ በቄድሮንም ፡ ፈፋ ፡ አጠ
ገብ ፡ አቃጠለው ፥ አድቅቆም ፡ ትቢያ ፡ አደረ
ገው ፥ ትቢያውንም ፡ በሕዝብ ፡ መቃብር ፡ ላይ ፡
፯፤ ጣለው ። ሴቶቹም ፡ ለማምለኪያ ፡ ዐፀድ ፡ መጋ
ረጃ ፡ ይፈትሉበቸው ፡ የነበሩትን ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ያሉትን ፡ የሰዶማውያንን ፡
፰፤ ቤቶች ፡ አፈረሰ ። ካህናቱንም ፡ ሁሉ ፡ ከይ
ሁዳ ፡ ከተሞች ፡ አወጣቸው ፤ ከጌባም ፡ጀምሮ ፡
እስከ ፡ ቤርሳቤህ ፡ ድረስ ፡ ካህናት ፡ ያጥኑበት ፡
የነበረውን ፡ የኮረብታ ፡ መስገጃ ፡ ሁሉ ፡ ርኩስ ፡
አደረገው ። በከተማይቱም ፡ በር ፡ በግራ ፡ በኩል ፡
በነበረው ፡ በከተማይቱ ፡ ሹም ፡ በኢያሱ ፡ በር ፡
መግቢያ ፡ አጠገብ ፡ የነበሩትን ፡ የበሮቹን ፡ መስ
፱፤ ገጃዎች ፡ አፈረሰ ። የኮረብታው ፡ መስገጃዎች ፡
ካህናት ፡ ግን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ አይመጡም ፡ ነበር ፤
ብቻ ፡ በወንድሞቻቸው ፡ መካከል ፡ ቂጣ ፡ እን
፲፤ ጀራ ፡ ይበሉ ፡ ነበር ። ማንም ፡ ሰው ፡ ወንድ ፡
ልጁን ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ልጁን ፡ ለሞሎክ ፡ በእ
ሳት ፡ እንዳያሳልፍ ፡ በሄኖም ፡ ልጆች ፡ ሸለቆ ፡
፲፩፤ የነበረውን ፡ ቶፌትን ፡ ርኩስ ፡ አደረገው ። የይ
ሁዳም ፡ ነገሥታት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
መግቢያ ፡ አጠገብ ፡ በከተማው ፡ አቅራቢያ ፡
በነበረው ፡ በጃንደረባው ፡ በናታንሜሌክ ፡ መኖ
ሪያ ፡ አጠገብ ፡ ለፀሐይ ፡ የሰጡትን ፡ ፈረሶች ፡
አስወገደ ፤ የፀሐይንም ፡ ሰረገሎች ፡ በእሳት ፡
፲፪፤ አቃጠለ ። የይሁዳም ፡ ነገሥታት ፡ ያሠሩትን ፡
በአካዝ ፡ ቤት ፡ ሰገነት ፡ ላይ ፡ የነበሩትን ፡ መሠ
ዊያዎች ፥ ምናሴም ፡ ያሠራውን ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ቤት ፡ በሁለቱ ፡ ወለሎች ፡ ላይ ፡ የነበሩ
ትን ፡ መሠዊያዎች ፡ ንጉሡ ፡ አስፈረሳቸው ፥
አደቀቃቸውም ፥ ትቢያቸውንም ፡ በቄድሮን ፡
፲፫፤ ፈፋ ፡ ጣለ ። በኢየሩሳሌምም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡
በርኵሰት ፡ ተራራ ፡ ቀኝ ፡ የነበሩትን ፥ የእስራ
ኤል ፡ ንጉሥ ፡ ሰሎሞን ፡ ለሲዶናውያን ፡ ርኵ
ሰት ፡ ለአስታሮት ፡ ለሞዓብም ፡ ርኵሰት ፡ ለካ
ሞሽ ፡ ለአሞንም ፡ ልጆች ፡ ርኵሰት ፡ ለሚል
ኮም ፡ ያሠራቸውን ፡ መስገጃዎች ፡ ንጉሡ ፡
ርኩስ ፡ አደረገ ። ሐውልቶቹንም ፡ ሁሉ ፡ አደ ፲፬፤
ቀቀ ፥ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶቹንም ፡ ቈረጠ ፥ በስ
ፍራቸውም ፡ የሙታንን ፡ አጥንት ፡ ሞላበት ።
፲፭፤ ደግሞም ፡ በቤቴል ፡ የነበረውን ፡ መሠዊያ ፥
እስራኤልንም ፡ ያሳተ ፡ የናባጥ ፡ ልጅ ፡ ኢዮር
ብዓም ፡ ያሠራውን ፡ የኮረብታውን ፡ መስገጃ ፥
ይህን ፡ መሠዊያና ፡ መስገጃ ፡ አፈረሰ ፤ ድንጋ
ዮቹንም ፡ ሰባበረ ፥ አድቅቆም ፡ ትቢያ ፡ አደረ
ገው ፥ የማምለኪያ ፡ ዐፀዱንም ፡ አቃጠለው ።
፲፮፤ ኢዮስያስም ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ በተራራው ፡ የነበ
ሩትን ፡ መቃብሮች ፡ አየ ፤ ኢዮርብዓምም ፡ በበ
ዓል ፡ጊዜ ፡ በመሠዊያ ፡ አጠገብ ፡ ሲቆም ፡ እነ
ዚህን ፡ ነገሮች ፡ የተነበ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ሰው ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ እንደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ቃል ፥ ልኮ ፡ ከመቃብሮቹ ፡ አጥንቶቹን ፡
አስወጣ ፥ በመሠዊያውም ፡ ላይ ፡ አቃጠላቸው ፡
አረከሰውም ። ዘወርም ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ተናገ
ረው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ መቃብር ፡
፲፯፤ ዓይኖቹን ፡ አቅንቶ ፡— ያ ፡ የማየው ፡ የመታሰ
ቢያ ፡ ምልክት ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለ ። የዚያ
ችም ፡ ከተማ ፡ ሰዎች ፡— ከይሁዳ ፡ ወጥቶ ፡ በቤ
ቴል ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ ይህን ፡ ያደረግኸውን ፡
ነገር ፡ የተናገረው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡
፲፰፤ መቃብር ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ነገሩት ። እርሱም ፡—
ተዉት ፥ ማንም ፡ አጥንቱን ፡ አያንቀሳቅሰው ፡
አለ ፤ እነርሱም ፡ ከሰማርያ ፡ ከወጣው ፡ ከነቢዩ ፡
፲፱፤ አጥንት ፡ ጋር ፡ አጥንቱን ፡ ተዉ ። በሰማርያም ፡
ከተሞች ፡ የነበሩትን ፥ እግዚአብሔርን ፡ ያስቈ
ጡት ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ የሠሩ
ትን ፡ የኮረብታውን ፡ መስገጃዎች ፡ ኢዮስያስ ፡
አስወገዳቸው ፥ በቤቴልም ፡ እንዳደረገው ፡ ነገር ፡
፳፤ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ አደረገባቸው ። በዚያም ፡ የነበ
ሩትን ፡ የኮረብታውን ፡ መስገጃዎች ፡ ካህናት ፡
ሁሉ ፡ በመሠዊያዎቹ ፡ ላይ ፡ ገደላቸው ፥ የሰዎ
ቹንም ፡ አጥንት ፡ በመሠዊያዎቹ ፡ ላይ ፡ አቃ
ጠለ ። ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ተመለሰ ።
፳፩፤ ንጉሡም ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡— በዚህ ፡ በቃል ፡
ኪዳን ፡ መጽሐፍ ፡ እንደ ፡ ተጻፈው ፡ ለአምላክ
ችሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ፋሲካ ፡ አድርጉ ፡ ብሎ ፡
፳፪፤ አዘዛቸው ። እንደዚህም ፡ ያለ ፡ ፋሲካ ፡ በእስ
ራኤል ፡ ላይ ፡ ይፈርዱ ፡ ከነበሩ ፡ ከመሳፍንት ፡
ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ በእስራኤልና ፡ በይሁዳ ፡ ነገሥ
፳፫፤ ታት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ አልተፈሰከም ። ነገር ፡
ግን ፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮስያስ ፡ በአሥራ ፡
ስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ ይህ ፡ ፋሲካ ፡ በኢየሩሳ
ሌም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተፈሰከ ።
፳፬፤ ደግሞም ፡ ካህኑ ፡ ኬልቅያስ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ቤት ፡ ባገኘው ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈውን ፡
የሕጉን ፡ ቃል ፡ ያጸና ፡ ዘንድ ፥ መናፍስት ፡ ጠሪ
ዎቹንና ፡ ጠንቋዮቹን ፡ ተራፊምንና ፡ ጣዖታት
ንም ፡ በይሁዳ ፡ አገርና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የተገ
ኘውን ፡ ርኵሰት ፡ ሁሉ ፡ ኢዮስያስ ፡ አስወገደ ።
፳፭፤ እንደ ፡ ሙሴም ፡ ሕግ ፡ ሁሉ ፡ በፍጹም ፡ ልቡ ፡
በፍጹምም ፡ ነፍሱ ፡ በፍጹምም ፡ ኃይሉ ፡ ወደ ፡

እግዚአብሔርም ፡ የተመለሰ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ያለ ፡ ንጉሥ ፡ ከእርሱ ፡ አስቀድሞ ፡ አልነበረም ፤ እንደ ፡ እርሱም ፡ ያለ ፡ ንጉሥ ፡ ከእርሱ ፡ በኋላ ፡ አልተነሣም ።

፳፮ ነገር ፡ ግን ፡ ምናሴ ፡ ስላስቈጣው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ከነደደው ፡ ከታላቁ ፡ ቍጣው ፡ ትኵሳት ፡ አልተመለሰም ። ፳፯ እግዚአብሔርም ፡— እስራኤልን ፡ እንዳራቅሁት ፡ ይሁዳን ፡ ከፊቴ ፡ አርቀዋለሁ ፤ ይህችንም ፡ የመረጥኋትን ፡ ከተማ ፡ ኢየሩሳሌምንና ፡— ስሜ ፡ በዚያ ፡ ይሆናል ፡ ያልሁትን ፡ ቤት ፡ እጥላለሁ ፡ አለ ።

፳፰ የቀረውም ፡ የኢዮስያስ ፡ ነገር ፥ የሠራውም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፥ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ፳፱ በእርሱም ፡ ዘመን ፡ የግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ፈርዖን ፡ ኒካው ፡ ከአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ጋር ፡ ሊጋጠም ፡ ወደ ፡ ኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ ወጣ ፤ ንጉሡም ፡ ኢዮስያስ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሊጋጠም ፡ ወጣ ፤ ፈርዖንም ፡ በተገናኘው ፡ ጊዜ ፡ በመጊዶ ፡ ገደለው ። ፴ ከሞተም ፡ በኋላ ፡ ባሪያዎቹ ፡ በሰረገላው ፡ አድርገው ፡ ከመጊዶ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ አመጡት ፥ በመቃብሩም ፡ ቀበሩት ። የአገሩም ፡ ሰዎች ፡ የኢዮስያስን ፡ ልጅ ፡ ኢዮአካስን ፡ ወሰዱት ፥ ቀብተውም ፡ በአባቱ ፡ ፋንታ ፡ አነገሡት ።

፴፩ ኢዮአካስም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ ነገሠ ። እናቱም ፡ አሚጣል ፡ ትባል ፡ ነበር ፥ እርስዋም ፡ የልብና ፡ ሰው ፡ የኤርምያስ ፡ ልጅ ፡ ነበረች ። ፴፪ አባቶቹም ፡ እንዳደረጉ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ። ፴፫ በኢየሩሳሌምም ፡ እንዳይነግሥ ፡ ፈርዖን ፡ ኒካው ፡ በሐማት ፡ ምድር ፡ ባለችው ፡ በሪብላ ፡ አሰረው ፤ በምድሩም ፡ ላይ ፡ መቶ ፡ መክሊት ፡ ብርና ፡ አንድ ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፡ ፈሰሴ ፡ ጣለበት ። ፴፬ ፈርዖን ፡ ኒካውም ፡ የኢዮስያስን ፡ ልጅ ፡ ኤልያቄምን ፡ በአባቱ ፡ በኢዮስያስ ፡ ፋንታ ፡ አነገሠ ፥ ስሙንም ፡ ኢዮአቄም ፡ ብሎ ፡ ለወጠው ። ኢዮአካስንም ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ አፈለሰው ፤ በዚያም ፡ ሞተ ። ፴፭ ኢዮአቄምም ፡ ብሩንና ፡ ወርቁን ፡ ለፈርዖን ፡ ሰጠው ፤ እንደ ፡ ፈርዖንም ፡ ትእዛዝ ፡ ገንዘብ ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ምድሩን ፡ አስገበረ ፤ ለፈርዖን ፡ ኒካውም ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ከአገሩ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ግምጋሚው ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ አስከፈለ ።

፴፮ ኢዮአቄምም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ አሥራ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡ ዘቢዳ ፡ ትባል ፡ ነበር ፤ እርስዋም ፡ የሩማ ፡ ሰው ፡ የፈዳያ ፡ ልጅ ፡ ነበረች ። ፴፯ አባቶቹም ፡ እንዳደረጉ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ በእርሱም ፡ ዘመን ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ወጣ ፥ ኢዮአቄምም ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ተገዛለት ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ዘወር ፡ አለና ፡ ዐመፀበት ። ፪ እግዚአብሔርም ፡ የከለዳውያንንና ፡ የሶርያውያንን ፡ የሞዓባውያንንም ፡ የአሞንንም ፡ ልጆች ፡ አደጋ ፡ ጣዮች ፡ ሰደደበት ፤ በባሪያዎቹ ፡ በነቢያት ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ያጠፉት ፡ ዘንድ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ሰደዳቸው ። ፫ ፬ ምናሴ ፡ ስላደረገው ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ ስላፈሰሰውም ፡ ንጹሕ ፡ ደም ፥ ኢየሩሳሌምንም ፡ በንጹሕ ፡ ደም ፡ ስለ ፡ ሞላ ፥ ከፊቱ ፡ ያስወግዳቸው ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ሆነ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ይራራ ፡ ዘንድ ፡ አልወደደም ።

፭ የቀረውም ፡ የኢዮአቄም ፡ ነገር ፥ የሠራውም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፥ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ፮ ኢዮአቄምም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፤ ልጁም ፡ ዮአኪን ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ። ፯ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ለግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ የነበረውን ፡ ሁሉ ፡ ከግብጽ ፡ ወንዝ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ፡ ወስዶ ፡ ነበርና ፡ የግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ከአገሩ ፡ አልወጣም ።

፰ ዮአኪን ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የአሥራ ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡ ኔስታ ፡ ትባል ፡ ነበር ፤ እርስዋም ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ሰው ፡ የኤልናታን ፡ ልጅ ፡ ነበረች ። ፱ አባቱም ፡ እንዳደረገ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ።

፲ በዚያም ፡ ወራት ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ የናቡከደነፆር ፡ ባሪያዎች ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወጡ ፥ ከተማይቱም ፡ ተከበበች ። ፲፩ ባሪያዎቹም ፡ በከበቡአት ፡ ጊዜ ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ መጣ ። ፲፪ የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ ዮአኪንና ፡ እናቱ ፥ ባሪያዎቹም ፥ አለቆቹም ፥ ጃንደረቦቹም ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ወጡ ፤ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ በነገሠ ፡ በስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ ያዘው ። ፲፫ የእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ መዛግብትን ፡ ሁሉ ፡ የንጉሡም ፡ ቤት ፡ መዛግብትን ፡ ከዚያ ፡ አወጣ ፤ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ሰሎሞን ፡ በእግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ የሠራውን ፡ የወርቁን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ሰባበረ ። ፲፬ ኢየሩሳሌምንም ፡ ሁሉ ፥ አለቆቹንም ፡ ሁሉ ፥ ጽኑዓን ፡ ኃያላኑንም ፡ ሁሉ ፥ ጠራቢዎቹንም ፡ ሁሉ ፥ ብረት ፡ ሠራተኞቹን ፡ ሁሉ ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ምርኮኞች ፡ አፈለሰ ፤ ከድሆች ፡ ከአገሩ ፡ ሕዝብ ፡ በቀር ፡ ማንም ፡ አልቀረም ። ፲፭ ዮአኪንንም ፡ ወደ ፡ ባቢ

ሎን ፡ አፈለሰ ፤ የንጉሡንም ፡ እናት ፥ የንጉሡ
ንም ፡ ሚስቶች ፥ ጃንደረቦቹንም ፥ የአገሩንም ፡
ታላላቆች ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡
፲፮ ማረከ ። የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ብርቱዎቹንና ፡
ሰልፍ ፡ የሚችሉትን ፡ ሁሉ ፥ ኃያላኑን ፡ ሁሉ ፡
ሰባት ፡ ሺህ ፡ ያህል ፥ ጠራቢዎችና ፡ ብረት ፡
ሠራተኞችም ፡ አንድ ፡ ሺህ ፥ ወደ ፡ ባቢሎን ፡
፲፯ ማረከ ። የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ የዮአኪንን ፡
አጎት ፡ ማታንያን ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ አነገሠ ፥
ስሙንም ፡ ሴዴቅያስ ፡ ብሎ ፡ ለወጠው ።
፲፰ ሴዴቅያስ ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡
አንድ ፡ ዓመት ፡ ጐልማሳ ፡ ነበረ ፤ በኢየሩሳሌ
ምም ፡ አሥራ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡
አሚጣል ፡ የተባለች ፡ የልብና ፡ ሰው ፡ የኤር
፲፱ ምያስ ፡ ልጅ ፡ ነበረች ። ኢዮአቄምም ፡ እንዳ
ደረገ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደ
፳ ረገ ። ከፊቱ ፡ አውጥቶ ፡ እስኪጥላቸው ፡ ድረስ ፡
ይህ ፡ ነገር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በኢየሩሳ
ሌምና ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ሆኖአልና ፤ ሴዴቅያ
ስም ፡ በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ላይ ፡ ዐመፀ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

፩ ሴዴቅያስም ፡ በነገሠ ፡ በዘጠኝኛው ፡ ዓመት ፡
በአሥረኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአሥረኛው ፡
ቀን ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆርና ፡ ሠራ
ዊቱ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጥተው ፡
ከበቡአት ፤ በዙሪያዋም ፡ ዕርድ ፡ ሠሩባት ።
፪ ከተማይቱም ፡ እስከ ፡ ንጉሡ ፡ እስከ ፡ ሴዴቅ
ያስ ፡ እስከ ፡ አሥራ ፡ አንደኛው ፡ ዓመት ፡
፫ ድረስ ፡ ተከብባ ፡ ነበር ። በአራተኛውም ፡ ወር ፡
በዘጠኝኛው ፡ ቀን ፡ በከተማይቱ ፡ ራብ ፡ ጸንቶ ፡
ነበርና ፡ ለአገሩ ፡ ሰዎች ፡ እንጀራ ፡ ታጣ ።
፬ ከተማይቱም ፡ ተሰበረች ፥ ሰልፈኞችም ፡ ሁሉ ፡
በሁለት ፡ ቅጥር ፡ መካከል ፡ ባለው ፡ በር ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ አትክልት ፡ በሚወስደው ፡ መንገድ ፡
በሌሊት ፡ ሸሹ ፤ ከለዳውያንም ፡ በከተማይቱ ፡
ዙሪያ ፡ ነበሩ ፤ በዓረባም ፡ መንገድ ፡ ሄዱ ።
፭ የከለዳውያንም ፡ ሠራዊት ፡ ንጉሡን ፡ ተከታ
ተሉ ፥ በኢያሪኮም ፡ ሜዳ ፡ ያዙት ፤ ሠራዊ
ቱም ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ ተለይተው ፡ ተበትነው ፡
፮ ነበር ። ንጉሡንም ፡ ይዘው ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡
ወዳለበት ፡ ወደ ፡ ሪብላ ፡ አመጡት ፤ ፍርድም ፡
፯ ፈረዱበት ። የሴዴቅያስንም ፡ ልጆች ፡ በፊቱ ፡
ገደሉአቸው ፤ የሴዴቅያስንም ፡ ዓይኖች ፡
አወጡ ፥ በሰንሰለትም ፡ አሰሩት ፥ ወደ ፡ ባቢሎ
ንም ፡ ወሰዱት ።
፰ በባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ በናቡከደነፆር ፡ በአ
ሥራ ፡ ዘጠኝኛው ፡ ዓመት ፡ በአምስተኛው ፡
ወር ፡ ከወሩም ፡ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ የባቢሎን ፡
ንጉሥ ፡ ባሪያ ፡ የዘበኞቹ ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡
፱ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጣ ። የእግዚአብሔር
ንም ፡ ቤትና ፡ የንጉሡን ፡ ቤት ፡ አቃጠለ ፤
የኢየሩሳሌምንም ፡ ቤቶች ፡ ሁሉ ፥ ታላላቆቹን ፡
፲ ቤቶች ፡ ሁሉ ፥ በእሳት ፡ አቃጠለ ። ከዘበኞ
ቹም ፡ አለቃ ፡ ጋር ፡ የነበረው ፡ የከለዳውያን ፡
ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ የኢየሩሳሌምን ፡ ቅጥር ፡ ዙሪ
፲፩ ያዋን ፡ አፈረሱ ። የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ ናቡዘ
ረዳን ፡ በከተማይቱ ፡ ውስጥ ፡ የቀረውን ፡ ሕዝብ ፥
ሸሽተውም ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ የተጠጉ
፲፪ ትን ፥ የቀሩትንም ፡ ሕዝብ ፡ አፈለሰ ። የዘበኞ
ቹም ፡ አለቃ ፡ ከአገሩ ፡ ድሆች ፡ ወይን ፡ ተካ
ዮችና ፡ አራሾች ፡ እንዲሆኑ ፡ አስቀረ ።
፲፫ ከለዳውያንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
ውስጥ ፡ የነበሩትን ፡ የናስ ፡ ዓምዶች ፥ በእግዚአ
ብሔርም ፡ ቤት ፡ የነበሩትን ፡ መቀመጫዎችና ፡
የናስ ፡ ኵሬ ፡ ሰባበሩ ፥ ናሱንም ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡
፲፬ ወሰዱ ። ምንቸቶቹንና ፡ መጫሪያዎቹንም ፡ መኰ
ስተሪያዎቹንና ፡ ጭልፋዎቹንም ፡ የሚያገለግ
፲፭ ሉበትንም ፡ የናስ ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ወሰዱ ። የዘበ
ኞቹም ፡ አለቃ ፡ ማንደጃዎቹንና ፡ መቀመጫዎ
ቹን ፥ የወርቁን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ በወርቅ ፥ የብሩ
፲፮ ንም ፡ በብር ፡ አድርጎ ፡ ወሰደ ። ሰሎሞንም ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የሠራቸውን ፡ ሁለቱን ፡ ዓም
ዶች ፡ አንዱንም ፡ ኵሬ ፡ መቀመጫዎቹንም ፡
ወሰደ ፤ ለእነዚህ ፡ ዕቃዎች ፡ ሁሉ ፡ ናስ ፡
፲፯ ሚዛን ፡ አልነበረውም ። የአንዱም ፡ ዓምድ ፡
ቁመት ፡ አሥራ ፡ ስምንት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ የና
ስም ፡ ጕልላት ፡ ነበረበት ፤ የጕልላቱም ፡ ርዝ
መት ፡ ሦስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ በጕልላቱም ፡
ላይ ፡ በዙሪያው ፡ የናስ ፡ መርበብና ፡ ሮማኖች ፡
ነበሩ ፤ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ በሁለተኛው ፡
ዓምድ ፡ ላይ ፡ መርበብ ፡ ነበረበት ።
፲፰ የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ ታላቁን ፡ ካህን ፡ ሠራ
ያን ፡ ሁለተኛውንም ፡ ካህን ፡ ሶፎንያስን ፡ ሦስ
፲፱ ቱንም ፡ በረኞች ፡ ወሰደ ። ከከተማይቱም ፡
በሰልፈኞች ፡ ላይ ፡ ተሾመው ፡ ከነበሩት ፡ አን
ዱን ፡ ጃንደረብ ፥ በከተማይቱም ፡ የተገኙትን ፡
በንጉሡ ፡ ፊት ፡ የሚቆሙትን ፡ አምስቱን ፡
ሰዎች ፥ የአገሩንም ፡ ሕዝብ ፡ የሚያሰልፍ ፡
የሠራዊቱን ፡ አለቃ ፡ ጸሐፊ ፥ በከተማይቱም ፡
ከተገኙት ፡ ከአገሩ ፡ ሕዝብ ፡ ስድሳ ፡ ሰዎች ፡
፳ ወሰደ ። የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡
ወስዶ ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ወዳለበት ፡ ወደ ፡
፳፩ ሪብላ ፡ አመጣቸው ። የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡
መታቸው ፥ በሐማትም ፡ ምድር ፡ ባለችው ፡
በሪብላ ፡ ገደላቸው ። እንዲሁ ፡ ይሁዳ ፡ ከአ
ገሩ ፡ ተማረከ ።
፳፪ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ በይሁዳ ፡
ምድር ፡ በቀረው ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ የሳፋንን ፡
ልጅ ፡ የአኪቃምን ፡ ልጅ ፡ ጎዶልያስን ፡ አለቃ ፡
፳፫ አደረገው ። የጭፍሮቹም ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፥
የናታንያ ፡ ልጅ ፡ እስማኤል ፥ የቃሬያም ፡ ልጅ ፡
ዮሐናን ፥ የነጦፋዊውም ፡ የተንሑሜት ፡ ልጅ ፡
ሠራያ ፥ የማዕካታዊውም ፡ ልጅ ፡ ያእዛንያ ፥
ሰዎቻቸውም ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ጎዶልያስን ፡
እንደ ፡ ሾመ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ጎዶልያስ ፡
፳፬ ወደ ፡ ምጽጳ ፡ መጡ ። ጎዶልያስም ፡— ከከለዳ
ውያን ፡ ሎሌዎች ፡ የተነሣ ፡ አትፍሩ ፥ በአገሩ ፡

ተቀመጡ ፥ ለባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ተገዙ ፥
መልካምም ፡ ይሆንላችኋል ፡ ብሎ ፡ ለእነርሱና ፡
፳፭፤ ለሰዎቻቸው ፡ ማለላቸው ። በሰባተኛው ፡ ወር ፡
ግን ፡ የመንግሥት ፡ ዘር ፡ የነበረ ፡ የኤሊሳማ ፡
ልጅ ፡ የናታንያ ፡ ልጅ ፡ እስማኤል ፡ ከእርሱም ፡
ጋር ፡ አሥር ፡ ሰዎች ፡ መጥተው ፡ ጎዶልያስንና ፡
ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በምጽጳ ፡ የነበሩትን ፡ አይሁድ
ንና ፡ ከለዳውያንን ፡ እስኪሞቱ ፡ ድረስ ፡ መቱ
፳፮፤ አቸው ። ከለዳውያንንም ፡ ፈርተው ፡ ነበርና ፡
ከታናሹ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ድረስ ፡ ሕዝቡ ፡
ሁሉ ፡ የጭፍሮቹም ፡ አለቆች ፡ ተነሥተው ፡
ወደ ፡ ግብጽ ፡ መጡ ።
፳፯፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ዮአኪን ፡
በተማረከ ፡ በሠላሳ ፡ ሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ በአ
ሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በሀያ ፡
ሰባተኛው ፡ ቀን ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ዮርማሮ
ዴቅ ፡ በነገሠ ፡ በአንደኛው ፡ ዓመት ፡ የይሁዳን ፡
ንጉሥ ፡ ዮአኪንን ፡ ከወህኒ ፡ አወጣው ፤ በፍ ፳፰፤
ቅርም ፡ ተናገረው ፥ ዙፋኑንም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
በባቢሎን ፡ ከነበሩት ፡ ነገሥታት ፡ ዙፋን ፡ በላይ ፡
አደረገለት ። በወህኒም ፡ ውስጥ ፡ ለብሶት ፡ የነ ፳፱፤
በረውን ፡ ልብስ ፡ ለወጠለት ፤ ዮአኪንም ፡ በሕ
ይወቱ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ሁልጊዜ ፡ እን
ጀራ ፡ ይበላ ፡ ነበር ። ንጉሡም ፡ በሕይወቱ ፡ ፴፤
ዘመን ፡ ሁሉ ፡ የዘወትር ፡ ቀለብ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡
ይሰጠው ፡ ነበር ።

# መጽሐፈ ፡ ዜና ፡ መዋዕል ፡ ቀዳማዊ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፡፪፤ አዳም ፥ ሴት ፥ ሄኖስ ፥ ቃይናን ፥ መላል
፫፤ ኤል ፥ ያሬድ ፥ ሄኖክ ፥ ማቱሳላ ፥ ላሜሕ ፥
፬፤ ኖኅ ፥ ሴም ፥ ካም ፥ ያፌት ።
፭፤ የያፌት ፡ ልጆች ፤ ጋሜር ፥ ማጎግ ፥ ማዴ ፥
፮፤ ያዋን ፥ ቶቤል ፥ ሞሳሕ ፥ ቴራስ ። የጋሜርም ፡
፯፤ ልጆች ፤ አስከናዝ ፥ ሪፋት ፥ ቴርጋማ ። የያ
ዋንም ፡ ልጆች ፤ ኤሊሳ ፥ ተርሴስ ፥ ኪቲም ፥
ሮድኢ ።
፰፤ የካምም ፡ ልጆች ፤ ኩሽ ፥ ምጽራይም ፥ ፉጥ ፥
፱፤ ከነዓን ። የኩሽም ፡ ልጆች ፤ ሳባ ፥ ኤውላጥ ፥
ሰብታ ፥ ራዕማ ፥ ሰብቃታ ። የራዕማም ፡ ልጆች ፤
፲፤ ሳባ ፥ ድዳን ። ኩሽም ፡ ናምሩድን ፡ ወለደ ፤
እርሱም ፡ በምድር ፡ ኃያል ፡ መሆንን ፡ ጀመረ ።
፲፩፤ ምጽራይምም ፡ ሉዲምን ፥ ዐናሚምን ፥ ላሀ
፲፪፤ ቢምን ፥ ነፍተሂምን ፥ ፈትሩሲምን ፥ ፍልስጥ
ኤማውያን ፡ የወጡበትን ፡ ከስሉሂምን ፥ ከፍ
፲፫፤ ቶሪምን ፡ ወለደ ። ከነዓንም ፡ የበኵር ፡ ልጁን ፡
፲፬፤ ሲዶንን ፥ ኬጢን ፥ ኢያቡሳዊውን ፥ አሞራዊ
፲፭፤ ውን ፥ ጌርጌሳዊውን ፥ ኤዊያዊውን ፥ ዐርካዊ
፲፮፤ ውን ፥ ሲኒያዊውን ፥ አራዴዎንን ፥ ሰማሪዎ
ንን ፥ አማቲን ፡ ወለደ ።
፲፯፤ የሴምም ፡ ልጆች ፤ ኤላም ፥ አሦር ፥ አርፋክ
ስድ ፥ ሉድ ፥ አራም ፥ ዑፅ ፥ ሁል ፥ ጌቴር ፥
፲፰፤ ሞሳሕ ። አርፋክስድም ፡ ቃይንምን ፡ ወለደ ፤
ቃይንምም ፡ ሳላን ፡ ወለደ ፤ ሳላም ፡ ዔቦርን ፡
፲፱፤ ወለደ ። ለዔቦርም ፡ ሁለት ፡ ልጆች ፡ ተወለዱ
ለት ፤ በዘመኑ ፡ ምድር ፡ ተከፍላለችና ፡ የአን
ደኛው ፡ ስም ፡ ፋሌቅ ፡ ተባለ ፤ የወንድሙም ፡
፳፤ ስም ፡ ዮቅጣን ፡ ነበረ ። ዮቅጣንም ፡ አልሞዳ
፳፩፤ ድን ፥ ሣሌፍን ፥ ሐስረሞትን ፥ ያራሕን ፥ ሀዶራ
፳፪፤ ምን ፥ አውዛልን ፥ ደቅላን ፥ ዖባልን ፥ አቢማ
፳፫፤ ኤልን ፥ ሳባን ፥ ኦፈርን ፥ ኤውላጥን ፥ ዮባብን ፡
ወለደ ፤ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የዮቅጣን ፡ ልጆች ፡
ነበሩ ።
ሴም ፥ አርፋክስድ ፥ ሳላ ፥ ዔቦር ፥ ፋሌቅ ፥ ፳፬፤፳፭፤
ራግው ፥ ሴሮሕ ፥ ናኮር ፥ ታራ ፥ አብርሃም ፡ የተ ፳፮፤፳፯፤
ባለ ፡ አብራም ።
የአብርሃምም ፡ ልጆች ፤ ይስሐቅ ፥ እስማ ፳፰፤
ኤል ። ትውልዳቸውም ፡ እንደዚህ ፡ ነው ። ፳፱፤
የእስማኤል ፡ በኵር ፡ ልጅ ፡ ነባዮት ፤ ከዚህ ፡
በኋላ ፡ ቄዳር ፥ ነብዳኤል ፥ መብሳም ፥ ማስ ፴፤
ማዕ ፥ ዱማ ፥ ማሣ ፥ ኩዳን ፥ ቴማን ፥ ኢጡር ፥ ፴፩፤
ናፌስ ፥ ቄድማ ፤ እነዚህ ፡ የእስማኤል ፡ ልጆች ፡
ናቸው ።
የአብርሃምም ፡ ገረድ ፡ የኬጡራ ፡ ልጆች ፤ ፴፪፤
ዘምራን ፥ ዮቅሳን ፥ ሜዳን ፥ ምድያም ፥ የስ
ቦቅ ፥ ስዌሕ ። የዮቅሳንም ፡ ልጆች ፤ ሳባ ፥
ድዳን ። የምድያምም ፡ ልጆች ፤ ጌፌር ፥ ዔፌር ፥ ፴፫፤
ሄኖኅ ፥ አቢዳዕ ፥ ኤልዳዓ ። እነዚህ ፡ ሁሉ ፡
የኬጡራ ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ።
አብርሃምም ፡ ይስሐቅን ፡ ወለደ ። የይስሐ ፴፬፤
ቅም ፡ ልጆች ፡ ዔሳውና ፡ እስራኤል ፡ ነበሩ ።
የዔሳው ፡ ልጆች ፤ ኤልፋዝ ፥ ራጉኤል ፥ ፴፭፤
የዑስ ፥ የዕላም ፥ ቆሬ ። የኤልፋዝ ፡ ልጆች ፤ ፴፮፤
ቴማን ፥ አማር ፥ ስፎ ፥ ጎቶም ፥ ቄኔዝ ፥ ቲም
ናዕ ፥ አማሌቅ ። የራጉኤል ፡ ልጆች ፤ ናሖት ፥ ፴፯፤
ዛራ ፥ ሣማ ፥ ሚዛሀ ።
የሴይርም ፡ ልጆች ፤ ሎጣን ፥ ሦባል ፥ ጽብ ፴፰፤
ዖን ፥ ዓና ፥ ዲሶን ፥ ኤጽር ፥ ዲሳን ። የሎጣ ፴፱፤
ንም ፡ ልጆች ፤ ሖሪ ፥ ሄማም ፤ ቲሞናዕ ፡ የሎጣን ፡
እኅት ፡ ነበረች ። የሦባል ፡ ልጆች ፤ ዓልዋን ፥ ማኔ ፵፤
ሐት ፥ ዔባል ፥ ስፎ ፥ አውናም ። የጽብዖንም ፡
ልጆች ፤ አያ ፥ ዓና ። የዓና ፡ ልጅ ፤ ዲሶን ። የዲሶ ፵፩፤
ንም ፡ ልጆች ፤ ሔምዳን ፥ ኤስባን ፥ ይትራን ፥
ክራን ። የኤጽር ፡ ልጆች ፤ ቢልሐን ፥ ዛዕዋን ፥ ፵፪፤
ዓቃን ። የዲሳን ፡ ልጆች ፤ ዑፅ ፥ አራን ።
በእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ገና ፡ ንጉሥ ፡ ፵፫፤
ሳይነግሥ ፡ በኤዶምያስ ፡ ምድር ፡ የነገሡ ፡ ነገ
ሥታት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። የቢዖር ፡ ልጅ ፡
ባላቅ ፤ የከተማይቱም ፡ ስም ፡ ዲንሃባ ፡ ነበረ ።

ተቀመጡ ÷ ለባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ተገዙ ÷ መልካምም ፡ ይሆንላችኋል ፡ ብሎ ፡ ለእነርሱና ፡ ፳፭፤ ለሰዎቻቸው ፡ ማለላቸው ። በሰባተኛው ፡ ወር ፡ ግን ፡ የመንግሥት ፡ ዘር ፡ የነበረ ፡ የኤሊሳማ ፡ ልጅ ፡ የናታንያ ፡ ልጅ ፡ እስማኤል ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ አሥር ፡ ሰዎች ፡ መጥተው ፡ ጎዶልያስንና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በምጽጳ ፡ የነበሩትን ፡ አይሁድ ንና ፡ ከለዳውያንን ፡ እስኪሞቱ ፡ ድረስ ፡ መቱ ፳፮፤ አቸው ። ከለዳውያንንም ፡ ፈርተው ፡ ነበርና ፡ ከታናሹ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ድረስ ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ የጭፍሮቹም ፡ አለቆች ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ መጡ ።

፳፯፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ዮአኪን ፡ በተማረከ ፡ በሠላሳ ፡ ሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ በአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በሀያ ፡ ሰባተኛው ፡ ቀን ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ዮርማሮዴቅ ፡ በነገሠ ፡ በአንደኛው ፡ ዓመት ፡ የይሁዳን ፡ ንጉሥ ፡ ዮአኪንን ፡ ከወህኒ ፡ አወጣው ፤ በፍ ፳፰፤ ቅርም ፡ ተናገረው ÷ ዙፋኑንም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በባቢሎን ፡ ከነበሩት ፡ ነገሥታት ፡ ዙፋን ፡ በላይ ፡ አደረገለት ። በወህኒም ፡ ውስጥ ፡ ለብሶት ፡ የነ ፳፱፤ በረውን ፡ ልብስ ፡ ለወጠለት ፤ ዮአኪንም ፡ በሕይወቱ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ሁልጊዜ ፡ እንጀራ ፡ ይበላ ፡ ነበር ። ንጉሡም ፡ በሕይወቱ ፡ ፴፤ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ የዘወትር ፡ ቀለብ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ይሰጠው ፡ ነበር ።

# መጽሐፈ ፡ ዜና ፡ መዋዕል ፡ ቀዳማዊ ።

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤፪፤ አዳም ÷ ሴት ÷ ሄኖስ ÷ ቃይናን ÷ መላልኤል ÷ ያሬድ ÷ ሄኖክ ÷ ማቱሳላ ÷ ላሜሕ ÷ ፫፤ ፬፤ ኖኅ ÷ ሴም ÷ ካም ÷ ያፌት ።

፭፤ የያፌት ፡ ልጆች ፤ ጋሜር ÷ ማጎግ ÷ ማዴ ÷ ፮፤ ያዋን ÷ ቶቤል ÷ ሞሳሕ ÷ ቴራስ ። የጋሜርም ፡ ፯፤ ልጆች ፤ አስከናዝ ÷ ሪፋት ÷ ቴርጋማ ። የያዋንም ፡ ልጆች ፤ ኤሊሳ ÷ ተርሴስ ÷ ኪቲም ÷ ሮድኢ ።

፰፤ የካምም ፡ ልጆች ፤ ኩሽ ÷ ምጽራይም ÷ ፉጥ ÷ ፱፤ ከነዓን ። የኩሽም ፡ ልጆች ፤ ሳባ ÷ ኤውላጥ ÷ ሰብታ ÷ ራዕማ ÷ ሰብቃታ ። የራዕማም ፡ ልጆች ፤ ፲፤ ሳባ ÷ ድዳን ። ኩሽም ፡ ናምሩድን ፡ ወለደ ፤ እርሱም ፡ በምድር ፡ ኃያል ፡ መሆንን ፡ ጀመረ ። ፲፩፤ ምጽራይምም ፡ ሉዲምን ÷ ዐናሚምን ÷ ላህ ፲፪፤ ቢምን ÷ ነፍተሂምን ÷ ፈትሩሲምን ÷ ፍልስጥኤማውያን ፡ የወጡበትን ፡ ከስሉሂምን ÷ ከፍ ፲፫፤ ቶሪምን ፡ ወለደ ። ከነዓንም ፡ የበኵር ፡ ልጁን ፡ ፲፬፤ ሲዶንን ÷ ኬጢን ÷ ኢያቡሳዊውን ÷ አሞራዊ ፲፭፤ ውን ÷ ጌርጌሳዊውን ÷ ኤዊያዊውን ÷ ዐርካዊ ፲፮፤ ውን ÷ ሲኒያዊውን ÷ አራዴዎንን ÷ ሰማሪዎንን ÷ አማቲን ፡ ወለደ ።

፲፯፤ የሴምም ፡ ልጆች ፤ ኤላም ÷ አሦር ÷ አርፋክስድ ÷ ሉድ ÷ አራም ÷ ዑፅ ÷ ሁል ÷ ጌቴር ÷ ፲፰፤ ሞሳሕ ። አርፋክስድም ፡ ቃይንምን ፡ ወለደ ፤ ቃይንምም ፡ ሳላን ፡ ወለደ ፤ ሳላም ፡ ዔቦርን ፡ ፲፱፤ ወለደ ። ለዔቦርም ፡ ሁለት ፡ ልጆች ፡ ተወለዱለት ፤ በዘመኑ ፡ ምድር ፡ ተከፍላለችና ፡ የአንደኛው ፡ ስም ፡ ፋሌቅ ፡ ተባለ ፤ የወንድሙም ፡ ፳፤ ስም ፡ ዮቅጣን ፡ ነበረ ። ዮቅጣንም ፡ አልሞዳ ፳፩፤ ድን ÷ ሣሌፍን ÷ ሐስረሞትን ÷ ያራሕን ÷ ሀዶራ ፳፪፤ ምን ÷ አውዛልን ÷ ደቅላን ÷ ዖባልን ÷ አቢማ ፳፫፤ ኤልን ÷ ሳባን ÷ አፊርን ÷ ኤውላጥን ÷ ዮባብን ፡ ወለደ ፤ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የዮቅጣን ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ።

፳፬፤፳፭፤ ሴም ÷ አርፋክስድ ÷ ሳላ ÷ ዔቦር ÷ ፋሌቅ ÷ ፳፮፤፳፯፤ ራግው ÷ ሴሮሕ ÷ ናኮር ÷ ታራ ÷ አብርሃም ፡ የተባለ ፡ አብራም ።

፳፰፤ የአብርሃምም ፡ ልጆች ፤ ይስሐቅ ÷ እስማ ፳፱፤ ኤል ። ትውልዳቸውም ፡ እንደዚህ ፡ ነው ። የእስማኤል ፡ በኵር ፡ ልጅ ፡ ነባዮት ፤ ከዚህ ፡ ፴፤ በኋላ ፡ ቄዳር ÷ ነብዳኤል ÷ መብሳም ÷ ማስ ፴፩፤ ማዕ ÷ ዱማ ÷ ማሣ ÷ ኩዳን ÷ ቴማን ÷ ኢጡር ÷ ናፌስ ÷ ቄድማ ፤ እነዚህ ፡ የእስማኤል ፡ ልጆች ፡ ናቸው ።

፴፪፤ የአብርሃምም ፡ ገረድ ፡ የኬጡራ ፡ ልጆች ፤ ዘምራን ÷ ዮቅሳን ÷ ሜዳን ÷ ምድያም ÷ የስበቅ ÷ ስዌሕ ። የዮቅሳንም ፡ ልጆች ፤ ሳባ ÷ ፴፫፤ ድዳን ። የምድያምም ፡ ልጆች ፤ ጌፌር ÷ ዔፌር ÷ ሄኖኅ ÷ አቢዳዕ ÷ ኤልዳዓ ። እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የኬጡራ ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ።

፴፬፤ አብርሃምም ፡ ይስሐቅን ፡ ወለደ ። የይስሐቅም ፡ ልጆች ፡ ዔሳውና ፡ እስራኤል ፡ ነበሩ ።

፴፭፤ የዔሳው ፡ ልጆች ፤ ኤልፋዝ ÷ ራጉኤል ÷ ፴፮፤ የዑስ ÷ የዕላም ÷ ቆሬ ። የኤልፋዝ ፡ ልጆች ፤ ቴማን ÷ አማር ÷ ስፎ ÷ ጎቶም ÷ ቄኔዝ ÷ ቲምናዕ ÷ አማሌቅ ። የራጉኤል ፡ ልጆች ፤ ናሖት ÷ ፴፯፤ ዛራ ÷ ሣማ ÷ ሚዛህ ።

፴፰፤ የሴይርም ፡ ልጆች ፤ ሎጣን ÷ ሦባል ÷ ጽብ ፴፱፤ ዖን ÷ ዓና ÷ ዲሶን ÷ ኤጽር ÷ ዲሳን ። የሎጣንም ፡ ልጆች ፤ ሖሪ ÷ ሄማም ፤ ቲሞናዕ ፡ የሎጣን ፡ እኅት ፡ ነበረች ። የሦባል ፡ ልጆች ፤ ዓልዋን ÷ ማኔ ፵፤ ሐት ÷ ዔባል ÷ ስፎ ÷ አውናም ። የጽብዖንም ፡ ልጆች ፤ አያ ÷ ዓና ። የዓና ፡ ልጅ ፤ ዲሶን ። የዲሶ ፵፩፤ ንም ፡ ልጆች ፤ ሔምዳን ÷ ኤስባን ÷ ይትራን ÷ ክራን ። የኤጽር ፡ ልጆች ፤ ቢልሐን ÷ ዛዕዋን ÷ ፵፪፤ ዓቃን ። የዲሳን ፡ ልጆች ፤ ዑፅ ÷ አራን ።

፵፫፤ በእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ገና ፡ ንጉሥ ፡ ሳይነግሥ ፡ በኤዶምያስ ፡ ምድር ፡ የነገሡ ፡ ነገሥታት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። የቢዖር ፡ ልጅ ፡ ባላቅ ፤ የከተማይቱም ፡ ስም ፡ ዲንሃባ ፡ ነበረ ።

፵፬ ባላቅም ፡ ሞተ ÷ በእርሱም ፡ ፋንታ ፡ የባሶራ ፡
፵፭ ሰው ፡ የዛራ ፡ ልጅ ፡ ኢዮባብ ፡ ነገሠ ። ኢዮባ
ብም ፡ ሞተ ÷ በእርሱም ፡ ፋንታ ፡ የቴማን ፡
፵፮ አገር ፡ ሰው ፡ ሑሳም ፡ ነገሠ ። ሑሳምም ፡ ሞተ ÷
በእርሱም ፡ ፋንታ ፡ በሞዓብ ፡ ሜዳ ፡ ምድያ
ምን ፡ የመታው ፡ የባዳድ ፡ ልጅ ፡ ሃዳድ ፡ ነገሠ ፤
፵፯ የከተማይቱም ፡ ስም ፡ ዓዊት ፡ ነበረ ። ሃዳድም ፡
ሞተ ÷ በእርሱም ፡ ፋንታ ፡ የመሥሬቃ ፡ ሰው ፡
፵፰ ሠምላ ፡ ነገሠ ። ሠምላም ፡ ሞተ ÷ በእርሱም ፡
ፋንታ ፡ በወንዙ ፡ አጠገብ ፡ ያለችው ፡ የረሆቦት ፡
፵፱ ሰው ፡ ሳኡል ፡ ነገሠ ። ሳኡልም ፡ ሞተ ÷ በእ
ርሱም ፡ ፋንታ ፡ የዓክቦር ፡ ልጅ ፡ በኣልሐናን ፡
፶ ነገሠ ። በኣልሐናንም ፡ ሞተ ÷ በእርሱም ፡
ፋንታ ፡ ሃዳድ ፡ ነገሠ ፤ የከተማይቱም ፡ ስም ፡
ፋዑ ፡ ነበረ ፤ ሚስቱም ፡ የሜዛሃብ ፡ ልጅ ፡ የመ
ጥሬድ ፡ ልጅ ፡ መሄጣብኤል ፡ ነበረች ፤ ሃዳድም ፡
ሞተ ።

፶፩ የኤዶምያስም ፡ አለቆች ፡ እነዚህ ፡ ነበሩ ፤
ቲምናዕ ፡ አለቃ ÷ ዓልዋ ፡ አለቃ ÷ የቴት ፡ አለቃ ÷
፶፪ አህሊባማ ፡ አለቃ ÷ ኤላ ፡ አለቃ ÷ ፊኖን ፡
፶፫ አለቃ ÷ ቄኔዝ ፡ አለቃ ÷ ቴማን ፡ አለቃ ÷ ሚብ
፶፬ ሳር ፡ አለቃ ÷ መግዲኤል ፡ አለቃ ÷ ዒራም ፡
አለቃ ፤ እነዚህ ፡ የኤዶምያስ ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤
ሮቤል ÷ ስምዖን ÷ ሌዊ ÷ ይሁዳ ÷ ይሳኮር ÷ ዛብ
፪ ሎን ÷ ዳን ÷ ዮሴፍ ÷ ብንያም ÷ ንፍታሌም ÷
ጋድ ÷ አሴር ።
፫ የይሁዳ ፡ ልጆች ፤ ዔር ÷ አውናን ÷ ሴሎም ፤
እነዚህ ፡ ሦስቱ ፡ ከከነዓናዊቱ ፡ ከሴዋ ፡ ልጅ ፡
ተወለዱለት ። የይሁዳም ፡ የበኵር ፡ ልጅ ፡ ዔር ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ነበረ ፤ ገደለውም ።
፬ ምራቱም ፡ ትዕማር ፡ ፋሬስንና ፡ ዛራን ፡ ወለደ
ችለት ፤ የይሁዳም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ አምስት ፡
ነበሩ ።
፭ የፋሬስ ፡ ልጆች ፤ ኤስሮም ÷ ሐሙል ።
፮ የዛራም ፡ ልጆች ፤ ዘምሪ ÷ ኤታን ÷ ሄማን ÷
፯ ከልኮል ÷ ዳራ ፤ ሁሉም ፡ አምስት ፡ ነበሩ ። የከ
ርሚም ፡ ልጅ ፡ እስራኤልን ፡ ያስጨነቀ ÷ እር
፰ ሙንም ፡ ሰርቆ ፡ የበደለ ፡ አካን ፡ ነበረ ። የኤታ
ንም ፡ ልጅ ፡ አዛርያ ፡ ነበረ ።
፱ ለኤስሮም ፡ የተወለዱለት ፡ ልጆች ፤ ይረሕም
፲ ኤል ÷ አራም ÷ ካልብ ፡ ነበሩ ። አራምም ፡ አሚ
ናዳብን ፡ ወለደ ፤ አሚናዳብም ፡ የይሁዳን ፡
፲፩ ልጆች ፡ አለቃ ፡ ነአሶንን ፡ ወለደ ፤ ነአሶንም ፡
ሰልሞንን ፡ ወለደ ፤ ሰልሞንም ፡ ቦዔዝን ፡ ወለደ ፤
፲፪ ቦዔዝም ፡ ኢዮቤድን ፡ ወለደ ፤ ኢዮቤድም ፡
፲፫ እሴይን ፡ ወለደ ፤ እሴይም ፡ የበኵር ፡ ልጁን ፡
ኤልያብን ÷ ሁለተኛውንም ፡ አሚናዳብን ÷ ሦስ
፲፬ ተኛውንም ፡ ሣማን ÷ አራተኛውንም ፡ ናትናኤ
፲፭ ልን ÷ አምስተኛውንም ፡ ራዳይን ÷ ስድስተኛ
ውንም ፡ አሳምን ÷ ሰባተኛውንም ፡ ዳዊትን ፡
፲፮ ወለደ ፤ እኅቶቻቸውም ፡ ጽሩያና ፡ አቢግያ ፡
ነበሩ ። የጽሩያም ፡ ልጆች ፡ አቢሳ ÷ ኢዮአብ ÷
፲፯ አሣሄል ፡ ሦስቱ ፡ ነበሩ ። አቢግያም ፡ አሜሳ
ይን ፡ ወለደች ፤ የአሜሳይም ፡ አባት ፡ እስማኤ
ላዊው ፡ ዬቴር ፡ ነበረ ።
፲፰ የኤስሮምም ፡ ልጅ ፡ ካሌብ ፡ ከሚስቱ ፡ ከዓ
ዙባ ፡ ከይሪዖትም ፡ ልጆች ፡ ወለደ ፤ ልጆች
፲፱ ዋም ፡ ያሳር ÷ ሶባብ ÷ አርዶን ፡ ነበሩ ። ዓዙ
ባም ፡ ሞተች ÷ ካሌብም ፡ ኤፍራታን ፡ አገባ ፤
፳ እርስዋም ፡ ሆርን ፡ ወለደችለት ። ሆርም ፡ ኡሪን ፡
ወለደ ÷ ኡሪም ፡ ባስልኤልን ፡ ወለደ ።
፳፩ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ኤስሮም ፡ ስድሳ ፡ ዓመት ፡
በሆነው ፡ ጊዜ ፡ ወዳገባት ፡ ወደ ፡ ገለዓድ ፡ አባት ፡
ወደ ፡ ማኪር ፡ ልጅ ፡ ገባ ፤ ሠጉብንም ፡ ወለደ
፳፪ ችለት ። ሠጉብም ፡ ኢያዕርን ፡ ወለደ ፤ ለእር
ሱም ፡ በገለዓድ ፡ ምድር ፡ ሀያ ፡ ሦስት ፡ ከተሞች ፡
፳፫ ነበሩት ። ጌሹርና ፡ አራምም ፡ የኢያዕርን ፡ ከተ
ሞች ፡ ከቄናትና ፡ ከመንደሮችዋ ፡ ጋር ፡ ስድሳ
ውን ፡ ከተሞች ፡ ወሰዱባቸው ። እነዚህ ፡ ሁሉ ፡
የገለዓድ ፡ አባት ፡ የማኪር ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ።
፳፬ ኤስሮምም ፡ በካሌብ ፡ ኤፍራታ ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡
የኤስሮም ፡ ሚስት ፡ አቢያ ፡ የቴቁሔን ፡ አባት ፡
አሽሑርን ፡ ወለደችለት ።
፳፭ የኤስሮምም ፡ የበኵር ፡ ልጁ ፡ የይረሕምኤል ፡
ልጆች ፡ በኵሩ ፡ ራም ÷ ቡናህ ÷ አሬን ÷ አጼም ÷
፳፮ አኪያ ፡ ነበሩ ። ለይረሕምኤልም ፡ ዓጣራ ፡ የተ
ባለች ፡ ሌላ ፡ ሚስት ፡ ነበረችው ፤ እርስዋም ፡
፳፯ የኦናም ፡ እናት ፡ ነበረች ። የይረሕምኤል ፡ የበ
ኵሩ ፡ የራም ፡ ልጆች ፡ መዓስ ÷ ያሚን ÷ ዔቄር ፡
፳፰ ነበሩ ። የኦናምም ፡ ልጆች ፡ ሸማይና ፡ ያዳ ፡
ነበሩ ። የሸማይ ፡ ልጆች ፡ ናዳብና ፡ አቢሱር ፡
፳፱ ነበሩ ። የአቢሱርም ፡ ሚስት ፡ አቢካኢል ፡ ነበ
፴ ረች ፤ አሕባንንና ፡ ሞሊድን ፡ ወለደችለት ። የና
ዳብም ፡ ልጆች ፡ ሴሌድና ፡ አፋይም ፡ ነበሩ ፤
፴፩ ሴሌድም ፡ ያለ ፡ ልጆች ፡ ሞተ ። የአፋይምም ፡
ልጅ ፡ ይሽዒ ÷ የይሽዒም ፡ ልጅ ፡ ሶሳን ÷ የሶሳ
፴፪ ንም ፡ ልጅ ፡ አሕላይ ፡ ነበረ ። የሸማይም ፡ ወን
ድም ፡ የያዳ ፡ ልጆች ፡ ዬቴርና ፡ ዮናታን ፡ ነበሩ ፤
፴፫ ዬቴርም ፡ ያለ ፡ ልጆች ፡ ሞተ ። የዮናታንም ፡
ልጆች ፡ ፌሌትና ፡ ዛዛ ፡ ነበሩ ፤ እነዚህ ፡ የይረ
፴፬ ሕምኤል ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ። ለሶሳንም ፡ ሴቶች ፡
ልጆች ፡ እንጂ ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ አልነበሩ
ትም ፤ ለሶሳንም ፡ ኢዮሄል ፡ የተባለ ፡ ግብጻዊ ፡
፴፭ አገልጋይ ፡ ነበረው ። ሶሳንም ፡ ለአገልጋዩ ፡
ለኢዮሄል ፡ ልጁን ፡ አጋባት ÷ እርስዋም ፡ ዓታ
፴፮ ይን ፡ ወለደችለት ። ዓታይም ፡ ናታንን ፡ ወለደ ፤
፴፯ ናታንም ፡ ዛባድን ፡ ወለደ ፤ ዛባድም ፡ ኤፍላ
ልን ፡ ወለደ ፤ ኤፍላልም ፡ ዖቤድን ፡ ወለደ ፤
፴፰ ዖቤድም ፡ ኢዩን ፡ ወለደ ፤ ኢዩም ፡ ዓዛርያስን ፡
፴፱ ወለደ ፤ ዓዛርያስም ፡ ኬሌስን ፡ ወለደ ፤ ኬሌስም ፡
፵ ኤልዓሣን ፡ ወለደ ፤ ኤልዓሣም ፡ ሲስማይን ፡
፵፩ ወለደ ፤ ሲስማይም ፡ ሰሎምን ፡ ወለደ ፤ ሰሎ
ምም ፡ የቃምያን ፡ ወለደ ፤ የቃምያም ፡ ኤሊሳ
ማን ፡ ወለደ ።
፵፪ የይረሕምኤልም ፡ ወንድም ፡ የካሌብ ፡ ልጆች ፡

በኵሩ ፡ የዚፍ ፡ አባት ፡ ሞሳ ÷ የኬብሮንም ፡
፵፫፤ አባት ፡ የመሪሳ ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ። የኬብሮ
ንም ፡ ልጆች ፡ ቆሬ ÷ ተፉዋ ÷ ሬቄም ÷ ሽማዕ ፡
፵፬፤ ነበሩ ። ሽማዕም ፡ የዮርቅዓምን ፡ አባት ፡ ረሐ
ምን ፡ ወለደ ፤ ሬቄምም ፡ ሽማይን ፡ ወለደ ።
፵፭፤ የሽማይም ፡ ልጅ ፡ ማዖን ፡ ነበረ ፤ ማዖንም ፡
፵፮፤ የቤት ፡ ጹር ፡ አባት ፡ ነበረ ። የካሌብም ፡ ቁባት ፡
ዔፋ ፡ ሐራንን ÷ ሞጻን ÷ ጋዜዝን ፡ ወለደች ።
፵፯፤ ሐራንም ፡ ጋዜዝን ፡ ወለደ ። የያህዳይም ፡
ልጆች ፡ ሬጌም ÷ ኢዮታም ÷ ጌሻን ÷ ፉሌጥ ÷
፵፰፤ ዔፋ ÷ ሸዓፍ ፡ ነበሩ ። የካሌብም ፡ ቁባት ፡ ማዕካ ፡
፵፱፤ ሼቤርንና ፡ ቲርሐናን ፡ ወለደች ። ደግሞም ፡
የመድማናን ፡ አባት ፡ ሽዓፍንና ፡ የመክቢናንና ፡
የጊብዓን ፡ አባት ፡ ሱሳን ፡ ወለደች ፤ የካሌብም ፡
ሴት ፡ ልጅ ፡ ዓክሳ ፡ ነበረች ።

፶፤ የካሌብ ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ የኤፍ
ራታ ፡ የበኵሩ ፡ የሆር ፡ ልጅ ፡ የቂርያትይዓሪም ፡
፶፩፤ አባት ፡ ሦባል ÷ የቤተ ፡ ልሔም ፡ አባት ፡ ሰል
፶፪፤ ሞን ÷ የቤት ፡ ጋዴር ፡ አባት ፡ ሐሬፍ ። ለቂር
ያትይዓሪምም ፡ አባት ፡ ለሦባል ፡ ልጆች ፡ ነበ
፶፫፤ ሩት ፤ ሀሮኤ ፡ የመናሕታውያን ፡ እኵሌታ ። የቂ
ርያትይዓሪምም ፡ ወገኖች ፤ ይትራውያን ÷ ፉታ
ውያን ÷ ሹማታውያን ÷ ሚሽራውያን ፤ ከእነ
ዚህም ፡ ጾርዓውያንና ፡ ኤሽታኦላውያን ፡ ወጡ ።
፶፬፤ የሰልሞንም ፡ ልጆች ፡ ቤተ ፡ ልሔም ÷ ነጦ
ፋውያን ÷ ዓጣሮትቤትዮአብ ÷ የመናሕታው
፶፭፤ ያን ፡ እኵሌታ ÷ ጾርዓውያን ፡ ነበሩ ። በያቤ
ጽም ፡ የተቀመጡ ፡ የጸሐፊዎች ፡ ወገኖች ፤ ቲር
ዓውያን ÷ ሺምዓታውያን ÷ ሡካታውያን ፡
ነበሩ ፤ እነዚህ ፡ ከሬካብ ፡ ቤት ፡ አባት ፡ ከሐማት ፡
የወጡ ፡ ቄናውያን ፡ ናቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፤ በኬብሮንም ፡ ለዳዊት ፡ የተወለዱለት ፡ ልጆች ፡
እነዚህ ፡ ናቸው ። በኵሩ ፡ አምኖን ፡ ከኢይዝ
ራኤላዊቱ ፡ ከአኪናሆም ÷ ሁለተኛውም ፡ ዳን
፪፤ ኤል ፡ ከቀርሜሎሳዊቱ ፡ ከአቢግያ ÷ ሦስተ
ኛው ፡ አቤሴሎም ፡ ከጌሹር ፡ ንጉሥ ፡ ከተል
ማይ ፡ ልጅ ፡ ከመዓካ ÷ አራተኛው ፡ አዶንያስ ፡
፫፤ ከአጊት ÷ አምስተኛው ፡ ሰፋጥያስ ፡ ከአቢጣል ÷
ስድስተኛው ፡ ይትረዓም ፡ ከሚስቱ ፡ ከዔግላ ።
፬፤ ስድስቱ ፡ በኬብሮን ፡ ተወለዱለት ፤ በዚያም ፡
ሰባት ፡ ዓመት ፡ ከስድስት ፡ ወር ፡ ነገሠ ፤ በኢየ
፭፤ ሩሳሌምም ፡ ሠላሳ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። እነ
ዚህ ፡ ደግሞ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተወለዱለት ፤ ከዓ
ሚኤል ፡ ልጅ ፡ ከቤርሳቤህ ÷ ሳሙስ ÷ ሶባብ ÷
፮፤ ናታን ÷ ሰሎሞን ÷ አራት ፤ ኢያቤሐር ÷ ኤሊ
፯፤ ሱዔ ÷ ኤሊፋላት ÷ ኖጋ ÷ ናፌቅ ÷ ያፍያ ÷
፰፤ ኤሊሳማ ÷ ኤሊዳሄ ÷ ኤሊፋላት ÷ ዘጠኝ ።
፱፤ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ከቁባቶች ፡ ልጆች ፡ በቀር ፡ የዳ
ዊት ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ፤ ትዕማርም ፡ እኅታቸው ፡
ነበረች ።

፲፤ የሰሎሞንም ፡ ልጅ ፡ ሮብዓም ፡ ነበረ ፤ ልጁ ፡
፲፩፤ አቢያ ÷ ልጁ ፡ አሳ ÷ ልጁ ፡ ኢዮሣፍጥ ÷ ልጁ ፡
ኢዮራም ÷ ልጁ ፡ አካዝያስ ÷ ልጁ ፡ ኢዮአስ ÷
፲፪፤ ልጁ ፡ አሜስያስ ÷ ልጁ ፡ ዓዛርያስ ÷ ልጁ ፡ ኢዮ
፲፫፤ አታም ÷ ልጁ ፡ አካዝ ÷ ልጁ ፡ ሕዝቅያስ ÷ ልጁ ፡
፲፬፤ ምናሴ ÷ ልጁ ፡ አሞጽ ÷ ልጁ ፡ ኢዮስያስ ።
፲፭፤ የኢዮስያስም ፡ ልጆች ፤ በኵሩ ፡ ዮሐናን ÷ ሁለ
ተኛውም ፡ ኢዮአቄም ÷ ሦስተኛውም ፡ ሴዴ
፲፮፤ ቅያስ ÷ አራተኛውም ፡ ሰሎም ። የኢዮአቄ
ምም ፡ ልጆች ፤ ልጁ ፡ ኢኮንያን ÷ ልጁ ፡ ሴዴ
፲፯፤ ቅያስ ። የምርኮኛውም ፡ የኢኮንያን ፡ ልጆች ፡
፲፰፤ ሰላትያል ÷ መልኪራም ÷ ፈዳያ ÷ ሼናጻር ÷
፲፱፤ ይቃምያ ÷ ሆሻማ ÷ ነዳብያ ፡ ነበሩ ። የፈዳያ ፡
ልጆች ፡ ዘሩባቤልና ፡ ሰሜኢ ፡ ነበሩ ፤ የዘ
ሩባቤልም ፡ ልጆች ፤ ሜሱላም ÷ ሐናንያ ÷
፳፤ እኅታቸውም ፡ ሰሎሚት ። ሐሹባ ÷ ኦሄል ÷
በራክያ ÷ ሐሳድያ ÷ ዮሻብሒሴድ ፡ አምስት ፡
፳፩፤ ናቸው ። የሐናንያም ፡ ልጆች ፡ ፈላጥያና ፡
የሻያ ፡ ነበሩ ። የረፋያ ፡ ልጆች ÷ የአርናን ፡
ልጆች ÷ የአብድዩ ፡ ልጆች ÷ የሴኬንያ ፡
፳፪፤ ልጆች ። የሴኬንያም ፡ ልጅ ፡ ሸማያ ፡ ነበረ ።
የሸማያም ፡ ልጆች ፡ ሐጡስ ÷ ይግአል ÷ ባር
፳፫፤ ያሕ ÷ ነዓርያ ÷ ሻፋጥ ፡ ስድስት ፡ ነበሩ ። የነዓር
ያም ፡ ልጆች ፡ ኤልዮዔናይ ÷ ሕዝቅያስ ÷ ዓዝ
፳፬፤ ሪቃም ፡ ሦስት ፡ ነበሩ ። የኤልዮዔናይም ፡ ልጆች ፡
ሆዳይዋ ÷ ኤልያሴብ ÷ ፌልያ ÷ ዓቁብ ÷ ዮሐ
ናን ÷ ደላያ ÷ ዓናኒ ፡ ሰባት ፡ ነበሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩፤ የይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ፋሬስ ÷ ኤስሮም ÷ ከርሚ ÷
፪፤ ሆር ÷ ሦባል ፡ ናቸው ። የሦባልም ፡ ልጅ ፡
ራያ ፡ ኢኤትን ፡ ወለደ ፤ ኢኤትም ፡ አሑማይ
ንና ፡ ላሃድን ፡ ወለደ ። እነዚህ ፡ የጾርዓውያን ፡
፫፤ ወገኖች ፡ ናቸው ። እነዚህም ፡ የኤጣም ፡ አባት ፡
ልጆች ፡ ናቸው ፤ ኢይዝራኤል ÷ ይሽማ ÷
፬፤ ይድባሽ ÷ እኅታቸውም ፡ ሃጽሌልፎኒ ። የጌዶ
ርም ፡ አባት ፡ ፋኑኤል ÷ የሑሻም ፡ አባት ፡
ኤጽር ፤ እነዚህ ፡ የቤተ ፡ ልሔም ፡ አባት ፡ የኤ
ፍራታ ፡ የበኵሩ ፡ የሆር ፡ ልጆች ፡ ናቸው ።
፭፤ ለቴቁሔም ፡ አባት ፡ ለአሽሑር ፡ ሔላና ፡ ነዕራ ፡
፮፤ የተባሉ ፡ ሁለት ፡ ሚስቶች ፡ ነበሩት ። ነዕራም ፡
አሑዛምን ÷ አፌርን ÷ ቴምኒን ÷ አሐሽታሪን ፡
ወለደችለት ። እነዚህ ፡ የነዕራ ፡ ልጆች ፡ ናቸው ።
፯፤ የሔላም ፡ ልጆች ፡ ዴሬት ÷ ይጽሐር ÷ ኤትናን ፡
፰፤ ናቸው ። ቆጽ ፡ ዓኑብን ÷ ጸቤባን ÷ የሃሩም
ንም ፡ ልጅ ፡ የአሐርሔልን ፡ ወገኖች ፡ ወለደ ።
፱፤ ያቤጽም ፡ ከወንድሞቹ ፡ ይልቅ ፡ የተከበረ ፡
ነበረ ፤ እናቱም ፡— በጣር ፡ ወልጄዋለሁና ፡
ብላ ፡ ስሙን ፡— ያቤጽ ፡ ብላ ፡ ጠራችው ።
፲፤ ያቤጽም ፡—አባክህ ÷ መባረክን ፡ ባርከኝ ÷ አገ
ሬንም ፡ አስፋው ፤ እጅህም ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡
ትሁን ፤ እንዳያሳዝነኝም ፡ ከክፋት ፡ ጠብቀኝ ፡
ብሎ ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ ጠራ ፤ እግዚአ
ብሔርም ፡ የለመነውን ፡ ሰጠው ።

፲፩፤ የሹሐም ፡ ወንድም ፡ ክሉብ ፡ የኤሽቶንን ፡
፲፪፤ አባት ፡ ምሒርን ፡ ወለደ ። ኤሽቶንም ፡ ቤትራ

ፋንና ፡ ፋሴሐን ፡ የዒርናሐሽንም ፡ አባት ፡
ተሒናን ፡ ወለደ ፤ እነዚህ ፡ የሬካ ፡ ሰዎች ፡
፲፫፤ ናቸው ። የቄኔዝም ፡ ልጆች ፡ ጎቶንያልና ፡
ሠራያ ፡ ነበሩ ። የጎቶንያልም ፡ ልጅ ፡ ሐታት ፡
፲፬፤ ነበረ ። መዖኖታይ ፡ ዖፍራን ፡ ወለደ ። ሠራ
ያም ፡ የጌሐራሺምን ፡ አባት ፡ ኢዮአብን ፡ ወለደ ፤
፲፭፤ እነርሱም ፡ ጠራቢዎች ፡ ነበሩ ። የዮፎኒም ፡
ልጅ ፡ የካሌብ ፡ ልጆች ፡ ዒሩ ፥ ኤላ ፥ ነዓም ፡
፲፮፤ ነበሩ ። የኤላም ፡ ልጅ ፡ ቄኔዝ ፡ ነበረ ። የይሃ
ሌልኤል ፡ ልጆች ፡ ዚፍ ፥ ዚፋ ፥ ቲርያ ፥ አሣ
፲፯፤ ርኤል ፡ ነበሩ ። የዕዝራም ፡ ልጆች ፡ ዬቴር ፥
ሜሬድ ፥ ዔፌር ፥ ያሎን ፡ ነበሩ ፤ ዬቴርም ፡
ማርያምን ፥ ሸማይን ፥ የኤሽትምዓን ፡ አባት ፡
፲፰፤ ይሽባን ፡ ወለደ ። አይሁዳዊቱም ፡ ሚስቱ ፡
የጌዶርን ፡ አባት ፡ ዬሬድን ፥ የሦኮንም ፡ አባት ፡
ሔቤርን ፥ የዛኖዋንም ፡ አባት ፡ ይቁቲኤልን ፡
ወለደች ። እነዚህም ፡ ሜሬድ ፡ ያገባት ፡ የፈር
፲፱፤ ዖን ፡ ልጅ ፡ የቢትያ ፡ ልጆች ፡ ናቸው ። የሆ
ዲያ ፡ ሚስት ፡ የነሐም ፡ እኅት ፡ ልጆች ፡ የገር
ሚው ፡ የቅዒላ ፡ አባትና ፡ ማዕካታዊው ፡ ኤሽ
፳፤ ትሞዓ ፡ ነበሩ ። የሺሞንም ፡ ልጆች ፡ አምኖን ፥
ሪና ፥ ቤንሐናን ፥ ቲሎን ፡ ነበሩ ። የይሽዒም ፡
፳፩፤ ልጆች ፡ ዞሔትና ፡ ቤንዞሔት ፡ ነበሩ ። የይሁ
ዳም ፡ ልጅ ፡ የሴሎም ፡ ልጆች ፡ የሌካ ፡ አባት ፡
ዔር ፥ የመሪሳ ፡ አባት ፡ ለዓዳ ፥ ከአሽቤዓ ፡
ቤት ፡ የሚሆኑ ፡ ጥሩ ፡ በፍታ ፡ የሚሠሩ ፡ ወገ
፳፪፤ ኖች ፥ ዮቂም ፥ የኮዜባ ፡ ሰዎች ፥ ኢዮአስ ፥
ሞዓብን ፡ የገዛ ፡ ሣራፍ ፥ ያሹቢሌሔም ፡ ነበሩ ።
፳፫፤ ይህ ፡ ዝና ፡ ከቀድሞ ፡ ጀምሮ ፡ ነበረ ። እነዚህ ፡
በነጣዒምና ፡ በጋዴራ ፡ የሚቀመጡ ፡ ሸክላ ፡
ሠራተኞች ፡ ነበሩ ። በዚያ ፡ በንጉሡ ፡ ዘንድ ፡
ስለ ፡ ሥራው ፡ ይቀመጡ ፡ ነበር ።
፳፬፤ የስምዖንም ፡ ልጆች ፤ ነሙኤል ፥ ያሚን ፥
፳፭፤ ያሪን ፥ ዛራ ፥ ሳኡል ፤ ልጁ ፡ ሰሎም ፥ ልጁ ፡
፳፮፤ መብሳም ፥ ልጁ ፡ ማስማዕ ። የማስማዕም ፡
ልጆች ፤ ልጁ ፡ ሃሙኤል ፥ ልጁ ፡ ዘኩር ፥ ልጁ ፡
፳፯፤ ሰሜኢ ። ለሰሜኢም ፡ አሥራ ፡ ስድስት ፡ ወን
ዶችና ፡ ስድስት ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ፤
ለወንድሞቹ ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ልጆች ፡ አልነበሩአ
ቸውም ፥ ወገናቸውም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ይሁዳ ፡
፳፰፤ ልጆች ፡ አልተባዙም ። በቤርሳቤህም ፥ በሞ
፳፱፤ ላዳ ፥ በሐጸርሹዓል ፥ በቢልሃ ፥ በዔጼም ፥
፴፤ በቶላድ ፥ በቤቱኤል ፥ በሔርማ ፥ በጺቅላግ ፥
፴፩፤ በቤትማርካቦት ፥ በሐጸርሱሲም ፥ በቤትቢሪ ፥
በሸዓራይም ፡ ይቀመጡ ፡ ነበር ። እስከ ፡ ዳዊ
ትም ፡ መንግሥት ፡ ድረስ ፡ ከተሞቻቸው ፡ እነ
፴፪፤ ዚህ ፡ ነበሩ ። መንደሮቻቸውም ፡ ኤጣም ፥
ዓይን ፥ ሬሞን ፥ ቶኬን ፥ ዓሻን ፥ አምስቱ ፡
፴፫፤ ከተሞች ፤ እስከ ፡ በኣልም ፡ ድረስ ፡ በእነዚህ ፡
ከተሞች ፡ ዙሪያ ፡ የነበሩ ፡ መንደሮቻቸው ፡
ሁሉ ፡ ነበሩ ። መቀመጫቸውና ፡ የትውልዳ
፴፬፤ ቸው ፡ መዝገቦች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። ምሾባብ ፥
፴፭፤ የምሌክ ፥ የአሚስያስ ፡ ልጅ ፡ ኢዮስያ ፥ ኢዮ
ኤል ፥ የዮሺብያ ፡ ልጅ ፥ የሠራያ ፡ ልጅ ፡ የዓሢ
፴፮፤ ኤል ፡ ልጅ ፡ ኢዩ ፥ ኤልዮዔናይ ፥ ያዕቆባ ፥
የሾሐያ ፥ ዓሣያ ፥ ዓዲዔል ፥ ዩሲምኤል ፥ በና
፴፯፤ ያስ ፥ የሺፊ ፡ ልጅ ፡ ዚዛ ፥ የአሎን ፡ ልጅ ፡
የይዳያ ፡ ልጅ ፡ የሺምሪ ፡ ልጅ ፡ የሸማያ ፡ ልጅ ፤
፴፰፤ እነዚህ ፡ በስማቸው ፡ የተጠሩ ፡ በወገኖቻቸው ፡
ላይ ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ፤ የአባቶቻቸውም ፡ ቤቶች ፡
፴፱፤ በዝተው ፡ ነበር ። ለመንጎቻቸው ፡ መሰምርያ ፡
ይሹ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ጌዶር ፡ መግቢያ ፡ እስከ ፡
፵፤ ሸለቆው ፡ ምሥራቅ ፡ ድረስ ፡ ሄዱ ። የለመለመ
ችም ፡ እጅግም ፡ ያማረች ፡ መሰምርያ ፡ አገኙ ፤
ምድሪቱም ፡ ሰፊና ፡ ጸጥተኛ ፡ ሰላም ፡ ያላትም ፡
ነበረች ፤ በቀድሞም ፡ ጊዜ ፡ በዚያ ፡ ተቀምጠው ፡
፵፩፤ የነበሩ ፡ ከካም ፡ ወገን ፡ ነበሩ ። እነዚህም ፡ በስ
ማቸው ፡ የተጻፉ ፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በሕዝቅ
ያስ ፡ ዘመን ፡ መጥተው ፡ ድንኳኖቻቸውንና ፡
በዚያ ፡ የተገኙትን ፡ ምዑናውያንን ፡ መቱ ፥
እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ ፈጽመው ፡ አጠፉአቸው ፤
በዚያም ፡ ለመንጎቻቸው ፡ መሰምርያ ፡ ነበረና ፡
፵፪፤ በስፍራቸው ፡ ተቀመጡ ። የስምዖንም ፡ ልጆች ፡
አምስት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ሴይር ፡ ተራራ ፡
ሄዱ ፤ አለቆቻቸውም ፡ የይሽዒ ፡ ልጆች ፥
ፈላጥያ ፥ ነዓርያ ፥ ረፋያ ፥ ዑዝኤል ፡ ነበሩ ።
፵፫፤ ያመለጡትንም ፡ የአማሌቃውያንን ፡ ቅሬታ ፡
መቱ ፥ በዚያም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ተቀም
ጠዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩፤ የእስራኤልም ፡ በኵር ፡ የሮቤል ፡ ልጆች ፡
እነዚህ ፡ ናቸው ። እርሱ ፡ የበኵር ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ የአባቱን ፡ ምንጣፍ ፡ ስላረከሰ ፡ ብኵ
ርናው ፡ ለእስራኤል ፡ ልጅ ፡ ለዮሴፍ ፡ ልጆች ፡
ተሰጠ ፤ ትውልዱ ፡ ግን ፡ ከብኵርና ፡ ጋር ፡ አል
፪፤ ተቈጠረም ። ይሁዳም ፡ በወንድሞቹ ፡ መካከል ፡
በረታ ፥ አለቃም ፡ ከእርሱ ፡ ሆነ ፤ ብኵርናው ፡
፫፤ ግን ፡ ለዮሴፍ ፡ ነበረ ። የእስራኤል ፡ በኵር ፡
የሮቤል ፡ ልጆች ፤ ሄኖኅ ፥ ፈሉሶ ፥ አስሮን ፥
፬፤ ከርሚ ፡ ነበሩ ። የኢዩኤል ፡ ልጆች ፤ ልጁ ፡
፭፤ ሸማያ ፥ ልጁ ፡ ጎግ ፥ ልጁ ፡ ሰሜኢ ፥ ልጁ ፡
፮፤ ሚካ ፥ ልጁ ፡ ራያ ፥ ልጁ ፡ ቢኤል ፥ የአሦር ፡
ንጉሥ ፡ ቴልጌልቴልፌልሶር ፡ የማረከው ፡ ልጁ ፡
ብኤራ ፤ እርሱ ፡ የሮቤል ፡ ነገድ ፡ አለቃ ፡ ነበረ ።
፯፤ ወንድሞቹ ፡ በየወገናቸው ፡ የትውልዶቻቸው ፡
መዝገብ ፡ በተቈጠረ ፡ ጊዜ ፤ አንደኛው ፡ ኢዮ
፰፤ ኤል ፥ ዘካርያስ ፥ እስከ ፡ ናባውና ፡ እስከ ፡ በአ
ልሜዎን ፡ ድረስ ፡ በአሮዔር ፡ የተቀመጠው ፡
የኢዮኤል ፡ ልጅ ፡ የሽማዕ ፡ ልጅ ፡ የዖዛዝ ፡
፱፤ ልጅ ፡ ቤላ ፤ በገለዓድ ፡ ምድር ፡ እንስሶቻቸው ፡
በዝተው ፡ ነበርና ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ከኤ
ፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምድረ ፡
፲፤ በዳው ፡ መግቢያ ፡ ድረስ ፡ ተቀመጠ ። በሳኦ
ልም ፡ ዘመን ፡ ከአጋራውያን ፡ ጋር ፡ ተዋጉ ፥
እነርሱም ፡ በእጃቸው ፡ ተመትተው ፡ ወደቁ ፤
በገለዓድ ፡ ምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ባለው ፡ አገር ፡
ሁሉ ፡ በድንኳኖቻቸው ፡ ተቀመጡ ።

፲፩፡ የጋድም ፡ ልጆች ፡ በባሳን ፡ ምድር ፡ እስከ ፡
ሰልካ ፡ ድረስ ፡ በአፋዛዣቸው ፡ ተቀመጡ ።
፲፪፡ አንደኛው ፡ ኢዮኤል ፥ ሁለተኛው ፡ ሳፋም ፥
፲፫፡ ያናይ ፥ ሳፋጥ ፡ በባሳን ፡ ተቀመጡ ። የአባቶቻ
ቸውም ፡ ቤቶች ፡ ወንድሞች ፡ ሚካኤል ፥ ሜሱ
ላም ፥ ሳባ ፥ ዮራይ ፥ ያካን ፥ ዙኤ ፥ አቤድ ፡
፲፬፡ ሰባት ፡ ነበሩ ። እነዚህም ፡ የቡዝ ፡ ልጅ ፡ የዩ
ዳይ ፡ ልጅ ፡ የኢዩሳይ ፡ ልጅ ፡ የሚካኤል ፡
ልጅ ፡ የገለዓድ ፡ ልጅ ፡ የኢዳይ ፡ ልጅ ፡ የዑሪ ፡
፲፭፡ ልጅ ፡ የአቢካኢል ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ። የአባቶቻ
ቸውም ፡ ቤቶች ፡ አለቃ ፡ የጉኒ ፡ ልጅ ፡ የአብ
፲፮፡ ዲኤል ፡ ልጅ ፡ ወንድም ፡ ነበረ ። በገለዓድም ፡
ምድር ፡ በባሳን ፡ በመንደሮቹም ፡ በሳሮንም ፡
መሰምርያዎች ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ዳርቻቸው ፡
፲፯፡ ድረስ ፡ ተቀምጠው ፡ ነበር ። እነዚህ ፡ ሁሉ ፡
በትውልዶቻቸው ፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮ
አታም ፡ ዘመንና ፡ በእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ በኢ
ዮርብዓም ፡ ዘመን ፡ ተቈጠሩ ።

፲፰፡ የሮቤልና ፡ የጋድ ፡ ልጆች ፡ የምናሴም ፡
ነገድ ፡ እኵሌታ ፥ ጽኑዓን ፥ ጋሻና ፡ ሰይፍ ፡
የሚይዙ ፥ ቀስተኞችም ፥ ሰልፍ ፡ የሚያውቁ ፡
ሰልፈኞችም ፥ አርባ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ሰባት ፡
፲፱፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ ነበሩ ። ከአጋራውያንና ፡ ከኢ
፳፡ ጡር ፡ ከናፌስና ፡ ከናዳብ ፡ ጋር ፡ ተዋጉ ። በሚዋ
ጉበትም ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኸዋ
ልና ፥ በእርሱም ፡ ታምነዋልና ፡ ተለመናቸው ፤
በላያቸውም ፡ ረዳት ፡ ሆናቸው ፥ አጋራውያ
ንና ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩትም ፡ ሁሉ ፡ በእ
፳፩፡ ጃቸው ፡ ተሰጡ ። ከከብቶቻቸውም ፡ አምሳ ፡
ሺህ ፡ ግመሎች ፥ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ሺህም ፡
በጎች ፥ ሁለት ፡ ሺህም ፡ አህዮች ፥ ከሰዎችም ፡
፳፪፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ ማረኩ ። ሰልፉ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ዘንድ ፡ ነበረና ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ተገድለው ፡
ወደቁ ፤ እስከ ፡ ምርኮም ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ በስ
ፍራቸው ፡ ተቀመጡ ።

፳፫፡ የምናሴ ፡ የነገድ ፡ እኵሌታ ፡ ልጆች ፡ በምድ
ሪቱ ፡ ተቀመጡ ። ከባሳንም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
በአልአርሞንዔምና ፡ እስከ ፡ ሳኔር ፡ እስከ ፡
፳፬፡ አርሞንዔም ፡ ተራራ ፡ ድረስ ፡ በዙ ። የአባቶ
ቻቸውም ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ እነዚህ ፡ ነበሩ ፤
ዔፌር ፥ ይሽዒ ፥ ኤሊኤል ፥ ዓዝርኤል ፥ ኤር
ምያ ፥ ሆዳይዋ ፥ ኢየድኤል ፤ እነርሱ ፡ ጽኑዓን ፡
ኀያላን ፡ የታወቁ ፡ ሰዎች ፡ የአባቶቻቸውም ፡
ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ።

፳፭፡ የአባቶቻቸውንም ፡ አምላክ ፡ በደሉ ፥ እግ
ዚአብሔርም ፡ ከፊታቸው ፡ በጠፉቸው ፡ በም
፳፮፡ ድሩ ፡ አሕዛብ ፡ አማልክት ፡ አመነዘሩ ። የእስራ
ኤልም ፡ አምላክ ፡ የአሦርን ፡ ንጉሥ ፡ የፎሐን ፡
መንፈስ ፥ የአሦርንም ፡ ንጉሥ ፡ የቴልጌልቴል
ፌልሶርን ፡ መንፈስ ፡ አስነሣ ፤ የሮቤልንና ፡ የጋ
ድን ፡ ልጆች ፡ የምናሴንም ፡ ነገድ ፡ እኵሌታ ፡
አፈለሰ ፥ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ወዳሉበት ፡ ወደ ፡ አላ
ሔና ፡ ወደ ፡ አቦር ፥ ወደ ፡ ሃራና ፡ ወደ ፡ ጎዛን ፡
ወንዝ ፡ አመጣቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

የሌዊ ፡ ልጆች ፤ ጌድሶን ፥ ቀዓት ፥ ሜራሪ ። ፩፡
የቀዓትም ፡ ልጆች ፤ እንበረም ፥ ይስዓር ፥ ኬብ ፪፡
ሮን ፥ ዑዝኤል ። የእንበረምም ፡ ልጆች ፤ አሮን ፥ ፫፡
ሙሴ ፥ ማርያም ። የአሮን ፡ ልጆች ፤ ናዳብ ፥
አብዩድ ፥ አልዓዛር ፥ ኢታምር ። አልዓዛር ፡ ፬፡
ፊንሐስን ፡ ወለደ ፤ ፊንሐስ ፡ አቢሱን ፡ ወለደ ፤
አቢሱም ፡ ቡቂን ፡ ወለደ ፤ ቡቂም ፡ ኦዚን ፡ ፭፡
ወለደ ፤ ኦዚም ፡ ዘራእያን ፡ ወለደ ፤ ዘራእያም ፡ ፮፡
መራዮትን ፡ ወለደ ፤ መራዮት ፡ አማርያን ፡ ፯፡
ወለደ ፤ አማርያም ፡ አኪጡብን ፡ ወለደ ፤ አኪ ፰፡
ጡብም ፡ ሳዶቅን ፡ ወለደ ፤ ሳዶቅም ፡ አኪማአ
ስን ፡ ወለደ ፤ አኪማአስም ፡ ዓዛርያስን ፡ ወለደ ፤ ፱፡
ዓዛርያስም ፡ ዮሐናንን ፡ ወለደ ፤ ዮሐናንም ፡ ፲፡
ዓዛርያስን ፡ ወለደ ፤ እርሱም ፡ ሰሎሞን ፡ በኢ
የሩሳሌም ፡ በሠራው ፡ ቤት ፡ ካህን ፡ ነበረ ፤ ዓዛ ፲፩፡
ርያስም ፡ አማርያን ፡ ወለደ ፤ አማርያም ፡ አኪ
ጡብን ፡ ወለደ ፤ አኪጡብም ፡ ሳዶቅን ፡ ወለደ ፤ ፲፪፡
ሳዶቅም ፡ ሰሎምን ፡ ወለደ ፤ ሰሎምም ፡ ኬል ፲፫፡
ቅያስን ፡ ወለደ ፤ ኬልቅያስም ፡ ዓዛርያስን ፡
ወለደ ፤ ዓዛርያስም ፡ ሠራያን ፡ ወለደ ፤ ሠራ ፲፬፡
ያም ፡ ኢዮሴዴቅን ፡ ወለደ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ፲፭፡
ይሁዳንና ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ በናቡከደነፆር ፡ እጅ ፡
በስማረከ ፡ ጊዜ ፡ ኢዮሴዴቅ ፡ ተማርኮ ፡ ሄደ ።

የሌዊ ፡ ልጆች ፤ ጌድሶን ፥ ቀዓት ፥ ሜራሪ ። ፲፮፡
የጌድሶንም ፡ ልጆች ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ሎቤኒ ፥ ፲፯፡
ሰሜኢ ። የቀዓትም ፡ ልጆች ፤ እንበረም ፥ ይስ ፲፰፡
ዓር ፥ ኬብሮን ፥ ዑዝኤል ፡ ነበሩ ። የሜራሪ ፡ ፲፱፡
ልጆች ፤ ሞሖሊ ፥ ሙሲ ። የሌዋውያን ፡ ወገ
ኖች ፡ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።
ከጌድሶን ፤ ልጁ ፡ ሎቤኒ ፥ ልጁ ፡ ኢኤት ፥ ልጁ ፡ ፳፡
ዘማት ፥ ልጁ ፡ ዮአክ ፥ ልጁ ፡ አዶ ፥ ልጁ ፡ ዛራ ፥ ፳፩፡
ልጁ ፡ ያትራይ ። የቀዓት ፡ ልጆች ፤ ልጁ ፡ አሚ ፳፪፡
ናዳብ ፥ ልጁ ፡ ቆሬ ፥ ልጁ ፡ አሴር ፥ ልጁ ፡ ፳፫፡
ሕልቃና ፥ ልጁ ፡ አቢሳፍ ፥ ልጁ ፡ አሴር ፥ ልጁ ፡ ፳፬፡
ኢኢት ፥ ልጁ ፡ ኡርኤል ፥ ልጁ ፡ ዖዝያ ፥
ልጁ ፡ ሳውል ። የሕልቃናም ፡ ልጆች ፤ አማሢ ፥ ፳፭፡
አኪሞት ። የሕልቃናም ፡ ልጆች ፤ ልጁ ፡ ሱፊ ፥ ፳፮፡
ልጁ ፡ ናሐት ፥ ልጁ ፡ ኤልያብ ፥ ልጁ ፡ ይሮ ፳፯፡
ሐም ፥ ልጁ ፡ ሕልቃና ። የሳሙኤልም ፡ ልጆች ፤ ፳፰፡
በኵሩ ፡ ኢዮኤል ፥ ሁለተኛውም ፡ አብያ ። የሜ ፳፱፡
ራሪ ፡ ልጆች ፤ ሞሖሊ ፥ ልጁ ፡ ሎቤኒ ፥ ልጁ ፡
ሰሜኢ ፥ ልጁ ፡ ዖዛ ፥ ልጁ ፡ ሳምዓ ፥ ልጁ ፡ ፴፡
ሐግያ ፥ ልጁ ፡ ዓሣያ ።

ዳዊትም ፡ ታቦቱ ፡ ዐርፎ ፡ ከተቀመጠ ፡ በኋላ ፡ ፴፩፡
በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ያቆማቸው ፡ የመዘም
ራን ፡ አለቆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። ሰሎሞንም ፡ ፴፪፡
የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ እስኪ
ሠራ ፡ ድረስ ፡ በመገናኛ ፡ ድንኳን ፡ ማደሪያ ፡
ፊት ፡ እያዜሙ ፡ ያገለግሉ ፡ ነበር ፤ በየተራቸ
ውም ፡ ያገለግሉ ፡ ነበር ። አገልጋዮቹና ፡ ልጆቹ ፡ ፴፫፡
እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ከቀዓት ፡ ልጆች ፡ ዘማሪው ፡
ኤማን ፡ ነበረ ፤ እርሱም ፡ የኢዮኤል ፡ ልጅ ፥

፴፬ የሳሙኤል ፡ ልጅ ÷ የሕልቃና ፡ ልጅ ÷ የይሮ
ሐም ፡ ልጅ ÷ የኤሊኤል ፡ ልጅ ÷ የቶዋ ፡ ልጅ ÷
፴፭ የሱፍ ፡ ልጅ ÷ የሕልቃና ፡ ልጅ ÷ የመሐት ፡
፴፮ ልጅ ÷ የአማሢ ፡ ልጅ ÷ የሕልቃና ፡ ልጅ ÷
የኢዮኤል ፡ ልጅ ÷ የዓዛርያስ ፡ ልጅ ÷ የሶፎን
፴፯ ያስ ፡ ልጅ ÷ የታሐት ፡ ልጅ ÷ የአሴር ፡ ልጅ ÷
፴፰ የአብያሳፍ ፡ ልጅ ÷ የቆሬ ፡ ልጅ ÷ የይስዓር ፡
ልጅ ÷ የቀዓት ፡ ልጅ ÷ የሌዊ ፡ ልጅ ÷ የእስራ
፴፱ ኤል ፡ ልጅ ፡ ነው ። በቀኙም ፡ የቆመ ፡ ወን
ድሙ ፡ አሳፍ ፡ ነበረ ፤ አሳፍም ፡ የበራክያ ፡ ልጅ ÷
፵ የሳምዓ ፡ ልጅ ÷ የሚክኤል ፡ ልጅ ÷ የበዓሤያ ፡
፵፩ ልጅ ÷ የመልክያ ፡ ልጅ ÷ የኤትኒ ፡ ልጅ ÷ የዛራ ፡
፵፪ ልጅ ÷ የዓዳያ ፡ ልጅ ÷ የኤታን ፡ ልጅ ÷ የዘ
፵፫ ማት ፡ ልጅ ÷ የሰሚኢ ፡ ልጅ ÷ የኢኤት ፡ ልጅ ÷
፵፬ የጌድሶን ፡ ልጅ ÷ የሌዊ ፡ ልጅ ፡ ነው ። በግራ
ቸውም ፡ በኩል ፡ ወንድሞቻቸው ፡ የሜራሪ ፡
ልጆች ፡ ነበሩ ፤ ኤታን ፡ የቂሳ ፡ ልጅ ÷ የአብዲ ፡
፵፭ ልጅ ÷ የማሉክ ፡ ልጅ ÷ የሐሽብያ ፡ ልጅ ÷ የአ
፵፮ ሜስያስ ፡ ልጅ ÷ የኬልቅያስ ፡ ልጅ ÷ የአማሲ ፡
፵፯ ልጅ ÷ የባኒ ፡ ልጅ ÷ የሴሜር ፡ ልጅ ÷ የሞ
ሖሊ ፡ ልጅ ÷ የሙሲ ፡ ልጅ ÷ የሜራሪ ፡ ልጅ ÷
፵፰ የሌዊ ፡ ልጅ ። ወንድሞቻቸውም ፡ ሌዋውያን ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ማደሪያ ፡ አገልግሎት ፡
ሁሉ ፡ ተሰጡ ።

፵፱ አሮንና ፡ ልጆቹ ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡
ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ፡ ለቅድስተ ፡
ቅዱሳን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ እስራኤልም ፡ ያስ
ተሰርይ ፡ ዘንድ ፡ ለሚቃጠለው ፡ መሥዋዕት ፡
በሚሆነው ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ ይሠዉ ፡ ነበር ÷
፶ በዕጣኑም ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ ያጥኑ ፡ ነበር ። የአ
ሮንም ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ልጁ ፡ አል
፶፩ ዓዛር ÷ ልጁ ፡ ፊንሐስ ÷ ልጁ ፡ አቢሱ ÷ ልጁ ፡
፶፪ ቡቂ ÷ ልጁ ፡ ኦዚ ÷ ልጁ ፡ ዘራእያ ÷ ልጁ ፡ መራ
፶፫ ዮት ÷ ልጁ ፡ አማርያ ÷ ልጁ ፡ አኪጦብ ÷ ልጁ ፡
ሳዶቅ ÷ ልጁ ፡ አኪማአስ ።

፶፬ ማደሪያዎቻቸውም ፡ በየሰፈራቸው ፡ በየዳር
ቻቸው ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ ለአሮን ፡ ልጆች ፡
ለቀዓት ፡ ወገኖች ፡ አንደኛው ፡ ዕጣ ፡ ነበረ ።
፶፭ ለእነርሱ ፡ በይሁዳ ፡ አገር ፡ ያለችውን ፡ ኬብሮ
ንን ÷ በእርስዋም ፡ ዙሪያ ፡ የነበረውን ፡ መሰም
፶፮ ርያ ፡ ሰጡ ፤ የከተማይቱን ፡ እርሻ ፡ ግን ፡ መን
ደሮችዋንም ፡ ለዮፎኒ ፡ ልጅ ፡ ለካሌብ ፡ ሰጡ ።
፶፯ ለአሮንም ፡ ልጆች ፡ የመማፀኛውን ፡ ከተሞች ÷
ኬብሮንን ÷ ልብናንና ፡ መሰምርያዋን ÷ ደግሞ ፡
፶፰ የቲርን ÷ ኤሽትሞዓንና ፡ መሰምርያዋን ÷ ሐሎ
ንንና ፡ መሰምርያዋን ÷ ዳቤርንና ፡ መሰምርያ
፶፱ ዋን ÷ ዓሳንንና ፡ መሰምርያዋን ÷ ቤትሳሚስንና ፡
፷ መሰምርያዋን ፤ ከብንያምም ፡ ነገድ ፡ ጌባንና ፡
መሰምርያዋን ÷ ጋሌማትንና ፡ መሰምርያዋን ÷
ዓናቶትንና ፡ መሰምርያዋን ፡ ሰጡ ። ከተሞቻ
ቸው ፡ ሁሉ ፡ በየወገናቸው ፡ አሥራ ፡ ሦስት ፡
ነበሩ ።

፷፩ ለቀሩትም ፡ ለቀዓት ፡ ልጆች ፡ ከነገዱ ፡ ወገን ፡
ከምናሴ ፡ ነገድ ፡ እኵሌታ ፡ አሥር ፡ ከተሞች ፡
በዕጣ ፡ ተሰጡ ። ፷፪ ለጌድሶንም ፡ ልጆች ፡ በየወ
ገናቸው ፡ ከይሳኮር ፡ ነገድ ÷ ከአሴርም ፡ ነገድ ÷
ከንፍታሌምም ፡ ነገድ ÷ በባሳንም ፡ ካለው ፡ ከም
ናሴ ፡ ነገድ ÷ አሥራ ፡ ሦስት ፡ ከተሞች ፡ ተሰጡ ።
፷፫ ለሜራሪ ፡ ልጆች ፡ በየወገናቸው ፡ ከሮቤል ፡
ነገድ ÷ ከጋድም ፡ ነገድ ÷ ከዛብሎንም ፡ ነገድ ÷
አሥራ ፡ ሁለት ፡ ከተሞች ፡ በዕጣ ፡ ተሰጡ ።
፷፬ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ለሌዋውያን ፡ ከተሞ
፷፭ ችን ፡ ከመሰምርያዎቻቸው ፡ ጋር ፡ ሰጡ ። ከይሁ
ዳም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ÷ ከስምዖንም ፡ ልጆች ፡
ነገድ ÷ ከብንያምም ፡ ልጆች ፡ ነገድ ÷ እነዚህን ፡
በስማቸው ፡ የተጠሩትን ፡ ከተሞች ፡ በዕጣ ፡
ሰጡ ።

፷፮ ከቀዓትም ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ ለአንዳንዶቹ ፡
ከኤፍሬም ፡ ነገድ ፡ ከተሞች ፡ ድርሻ ፡ ነበራቸው ።
፷፯ በተራራማው ፡ በኤፍሬም ፡ አገር ፡ ያሉትን ፡
የመማፀኛውን ፡ ከተሞች ፡ ሴኬምንና ፡ መሰም
ርያዋን ÷ ደግሞም ፡ ጌዝርንና ፡ መሰምርያዋን ÷
፷፰ ዮቅምዓምንና ፡ መሰምርያዋን ÷ ቤትሖሮንንና ፡
፷፱ መሰምርያዋን ÷ ኤሎንንና ፡ መሰምርያዋን ÷
ጋትሪሞንንና ፡ መሰምርያዋን ፡ ሰጡአቸው ።
፸ ከምናሴም ፡ ነገድ ፡ እኵሌታ ፡ ዓኔርንና ፡ መሰ
ምርያዋን ÷ ቢልዓምንና ፡ መሰምርያዋን ÷ ከቀ
ዓት ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ ለቀሩት ፡ ሰጡ ።

፸፩ ለጌድሶን ፡ ልጆች ፡ ከምናሴ ፡ ነገድ ፡ እኵ
ሌታ ፡ ወገን ፡ በባሳን ፡ ያለችው ፡ ጎላንና ፡ መሰ
፸፪ ምርያዋ ÷ አስታሮትና ፡ መሰምርያዋ ፤ ከይሳኮ
ርም ፡ ነገድ ፡ ቃዴስና ፡ መሰምርያዋ ÷ ዳብራ
፸፫ ትና ፡ መሰምርያዋ ÷ ራሞትና ፡ መሰምርያዋ ÷
፸፬ ዓኔምና ፡ መሰምርያዋ ፤ ከአሴርም ፡ ነገድ ፡ መዓ
ሳልና ፡ መሰምርያዋ ÷ ዓብዶንና ፡ መሰምርያዋ ÷
፸፭ ሑቆቅና ፡ መሰምርያዋ ÷ ረአብና ፡ መሰምር
፸፮ ያዋ ፤ ከንፍታሌምም ፡ ነገድ ፡ በገሊላ ፡ ያለችው ፡
ቃዴስና ፡ መሰምርያዋ ÷ ሐሞንና ፡ መሰምር
ያዋ ÷ ቂርያታይምና ፡ መሰምርያዋ ፡ ተሰጡ ።

፸፯ ከሌዋውያን ፡ ለቀሩት ፡ ለሜራሪ ፡ ልጆች ፡
ከዛብሎን ፡ ነገድ ፡ሬሞንና ፡ መሰምርያዋ ÷ ታቦ
፸፰ ርና ፡ መሰምርያዋ ፤ ከሮቤልም ፡ ነገድ ፡ በኢ
ያሪኮ ፡ አንጻር ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በምሥራቅ ፡
በኩል ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ያለችው ፡ ቦሶርና ፡
፸፱ መሰምርያዋ ÷ ያሳና ፡ መሰምርያዋ ÷ ቅዴሞ
ትና ፡ መሰምርያዋ ÷ ሜፍዓትና ፡ መሰምርያዋ ፤
፹ ከጋድም ፡ ነገድ ፡ በገለዓድ ፡ ያለችው ፡ ሬማ
ትና ፡ መሰምርያዋ ÷ መሃናይምና ፡ መሰምር
፹፩ ያዋ ÷ ሐሴቦንና ፡ መሰምርያዋ ÷ ኢያዜርና ፡
መሰምርያዋ ፡ ተሰጡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ የይሳኮርም ፡ ልጆች ÷ ቶላ ÷ ፉዋ ÷ ያሱብ ፡
፪ ሺምሮን ÷ አራት ፡ ናቸው ። የቶላም ፡ ልጆች ÷
ኦዚ ÷ ረፋያ ÷ ይሪኤል ÷ የሕማይ ÷ ይብሣም ÷
ሽሙኤል ÷ የአባታቸው ፡ የቶላ ፡ ቤት ፡ አለ
ቆች ÷ በትውልዳቸው ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡
ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ በዳዊት ፡ ዘመን ፡ ቍጥራቸው ፡

ህያ ፡ ሁለት ፡ ሺ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ነበረ ።
፫ የኦዚም ፡ ልጆች ፡ ይዝረሕያ ፤ የይዝረሕያም ፡
ልጆች ፡ ሚካኤል ፥ አብድዩ ፥ ኢዩኤል ፥ ይሺያ ፡
አምስት ፡ ናቸው ፤ ሁሉም ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ።
፬ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ በየትውልዳቸው ፡ በየአባቶቻ
ቸው ፡ ቤቶች ፡ ለሰልፍ ፡ የተዘጋጁ ፡ የሠራዊት ፡
ጭፍሮች ፡ ነበሩ ፤ ብዙም ፡ ሴቶችና ፡ ልጆች ፡
ነበሩአቸውና ፡ ሠላሳ ፡ ስድስት ፡ ሺ ፡ ነበሩ ።
፭ ወንድሞቻቸውም ፡ በይሳኮር ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡
ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡ ሰዎች ፡ በትውልዳቸው ፡
ሁሉ ፡ የተቈጠሩ ፡ሰማንያ ፡ ሰባት ፡ ሺ ፡ ነበሩ ።
፮ የብንያም ፡ ልጆች ፡ ቤላ ፥ ቤኬር ፥ ይዲኤል ፡
፯ ሦስት ፡ ነበሩ ። የቤላም ፡ ልጆች ፥ ኤሴቦን ፥
ኦዚ ፥ ዑዝኤል ፥ ኢያሪሙት ፥ ዒሪ ፥ አምስት ፡
ነበሩ ፤ የአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፥ ጽኑ
ዓን ፡ ኃያላን ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ በትውልድ ፡
የተቈጠሩ ፡ ህያ ፡ ሁለት ፡ ሺ ፡ ሠላሳ ፡ አራት ፡
፰ ነበሩ ። የቤኬርም ፡ ልጆች ፤ ዝሚራ ፥ ኢዮ
አስ ፥ አልዓዛር ፥ ኤልዮዔናይ ፥ ዖምሪ ፥ ኢያ
ሪሙት ፥ አብያ ፥ ዓናቶት ፥ ዓሌሜት ፤ እነዚህ ፡
፱ ሁሉ ፡ የቤኬር ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ። በየትውልዳ
ቸው ፡ መዝገብ ፡ የተቈጠሩ ፥ የአባቶቻቸው ፡
ቤቶች ፡ አለቆች ፥ ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡ ሰዎች ፡
፲ ህያ ፡ ሺ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። የይዲኤ
ልም ፡ ልጅ ፡ ቢልሐን ፡ ነበረ ፤ የቢልሐንም ፡
ልጆች ፡ የዑስ ፥ ብንያም ፥ ኤሁድ ፥ ክንዓና ፥
፲፩ ዜታን ፥ ተርሴስ ፥ አኪሳአር ፡ ነበሩ ። እነዚህ ፡
ሁሉ ፡ የይዲኤል ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ፤ በየአባቶቻ
ቸው ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፥ ጭፍራ ፡ እየሆኑ ፡ ወደ ፡
ሰልፍ ፡ የሚወጡ ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡ ሰዎች ፡
አሥራ ፡ ሰባት ፡ ሺ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።
፲፪ ደግሞም ፡ ሳፊን ፥ ሑፊም ፡ የዒር ፡ ልጆች ፥
ሑሺም ፡ የአሔር ፡ ልጆችም ፡ ነበሩ ።
፲፫ የንፍታሌም ፡ ልጆች ፥ ያሕጽኤል ፥ ጉኒ ፥
ዬጽር ፥ ሺሌም ፥ የባላ ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ።
፲፬ የምናሴ ፡ ልጆች ፡ ሶርያይቱ ፡ ቁባቱ ፡ የወለደ
ችለት ፡ እሥርኤልና ፡ የገለዓድ ፡ አባት ፡ ማኪር ፡
፲፭ ናቸው ። ማኪርም ፡ ከሑፊምና ፡ ከሳፊን ፡ ወገን ፡
ሚስት ፡ አገባ ፤ የእኅትዋም ፡ ስም ፡ መዓካ ፡
ነበረ ፤ የሁለተኛውም ፡ ስም ፡ ሰለጰዓድ ፡ ነበረ ፤
ለሰለጰዓድም ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ።
፲፮ የማኪርም ፡ ሚስት ፡ መዓካ ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፥
ስሙንም ፡ ፋሬስ ፡ ብላ ፡ ጠራችው ፤ የወንድሙም ፡
ስም ፡ ሱሮስ ፡ ነበረ ፤ ልጆቹም ፡ ኡላም ፥ ራቄም ፡
፲፯ ነበሩ ። የኡላምም ፡ ልጅ ፡ ባዳን ፡ ነበረ ፤ እነዚህ ፡
የምናሴ ፡ ልጅ ፡ የማኪር ፡ ልጅ ፡ የገለዓድ ፡ ልጆች ፡
፲፰ ነበሩ ። እኅቱ ፡ መለኬት ፡ ኢሱድን ፥ አቢዔዝ
፲፱ ርን ፥ መሕላን ፡ ወለደች ። የሸሚዳም ፡ ልጆች ፡
አሒያን ፥ ሴኬም ፥ ሊቅሒ ፥ አኒዓም ፡ ነበሩ ።
፳ የኤፍሬም ፡ ልጆች ፤ ሹቱላ ፥ ልጁ ፡ ባሬድ ፥
ልጁ ፡ ታሐት ፥ ልጁ ፡ ኤልዓዳ ፥ ልጁ ፡ ታሐት ፥
፳፩ ልጁ ፡ ዛባድ ፥ ልጁ ፡ ሹቱላ ፥ የአገሩም ፡ ተወ
ላጆች ፡ የጌት ፡ ሰዎች ፡ ከብቶቻቸውን ፡ ሊወ
ስዱ ፡ ወርደው ፡ ነበርና ፡ የገደሉአቸው ፡ ልጆቹ ፡
ኤድርና ፡ ኤልዓድ ፡ ነበሩ ። አባታቸውም ፡ ፳፪
ኤፍሬም ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ አለቀሰ ፥ ወንድሞቹም ፡
ሊያጽናኑት ፡ መጡ ። ወደ ፡ ሚስቱም ፡ ገባ ፥ ፳፫
አረገዘችም ፥ ወንድ ፡ ልጅም ፡ ወለደች ፤ በቤ
ቱም ፡ መከራ ፡ ሆኖአልና ፡ ስሙን ፡ በሪዓ ፡ ብሎ ፡
ጠራው ። ሴት ፡ ልጁም ፡ ታችኛውንና ፡ ላይ ፳፬
ኛውን ፡ ቤትሖሮንንና ፡ ኡዜንሼራን ፡ የሠራች ፡
ሲአራ ፡ ነበረች ። ወንዶች ፡ ልጆቹም ፡ ፋሬ ፥ ፳፭
ሬሴፍ ፥ ልጁ ፡ ቴላ ፥ ልጁ ፡ ታሐን ፥ ልጁ ፡ ፳፮
ለአዳን ፥ ልጁ ፡ ዓሚሁድ ፥ ልጁ ፡ ኤሊሳማ ፥
ልጁ ፡ ነዌ ፥ ልጁ ፡ ኢያሱ ። ፳፯
ግዛታቸውና ፡ ማደሪያቸው ፡ ቤቴልና ፡ መን ፳፰
ደሮችዋ ፥ በምሥራቅም ፡ በኩል ፡ ነዓራን ፥
በምዕራብም ፡ በኩል ፡ ጌዝርና ፡ መንደሮችዋ ፥
ደግሞ ፡ ሴኬምና ፡ መንደሮችዋ ፡ እስከ ፡ ጋዛና ፡
እስከ ፡ መንደሮችዋ ፡ ድረስ ፥ በምናሴም ፡ ፳፱
ልጆች ፡ ዳርቻ ፡ ቤትሳንና ፡ መንደሮችዋ ፥ ታዕ
ናክና ፡ መንደሮችዋ ፥ መጊዶና ፡ መንደሮችዋ ፥
ዶርና ፡ መንደሮችዋ ፡ ነበሩ ፤ በእነዚህ ፡ የእስ
ራኤል ፡ ልጅ ፡ የዮሴፍ ፡ ልጆች ፡ ተቀመጡ ።
የአሴር ፡ ልጆች ፤ ዩምና ፥ የሱዋ ፥ የሱዊ ፥ ፴
በሪዓ ፥ እኅታቸውም ፡ ሤራሕ ። የበሪዓም ፡ ፴፩
ልጆች ፤ ሔቤር ፥ የቢርዛዊት ፡ አባት ፡ የነበ
ረው ፡ መልኪኤል ። ሔቤርም ፡ ያፍሌጥን ፥ ፴፪
ሳሜርን ፥ ኮታምን ፥ እኅታቸውንም ፡ ሶላን ፡
ወለደ ። የያፍሌጥም ፡ ልጆች ፡ ፋሴክ ፥ ቢም ፴፫
ሃል ፥ ዓሲት ፡ ነበሩ ፤ እነዚህ ፡ የያፍሌጥ ፡
ልጆች ፡ ነበሩ ። የሳሜርም ፡ ልጆች ፡ አኪ ፥ ፴፬
ሮኦጋ ፥ ይሑባ ፥ አራም ፡ ነበሩ ። የወንድሙም ፡ ፴፭
የኤላም ፡ ልጆች ፡ ጾፋ ፥ ይምና ፥ ሰሌስ ፥ ዓማል ፡
ነበሩ ። የጾፋም ፡ ልጆች ፡ ሱዋ ፥ ሐርኔፍር ፥ ፴፮
ሦጋል ፥ ቤሪ ፥ ይምራ ፥ ቤጼር ፥ ሆድ ፥ ሳማ ፥ ፴፯
ሰሊሳ ፥ ይትራን ፥ ብኤራ ፡ ነበሩ ። የዬቴር ፡ ፴፰
ልጆች ፡ ዮሮኒ ፥ ፌስጳ ፥ አራ ፡ ነበሩ ።
የዑላ ፡ ልጆች ፡ ኤራ ፥ ሐኒኤል ፥ ሪጽያ ፡ ነበሩ ። ፴፱
እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የአሴር ፡ ልጆች ፥ የአባቶቻቸው ፡ ፵
ቤቶች ፡ አለቆች ፥ የተመረጡ ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያ
ላን ፡ ሰዎች ፥ የመኳንንቱ ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ።
በትውልዳቸውም ፡ በሰልፍ ፡ ለመዋጋት ፡ የተ
ቈጠሩ ፡ ህያ ፡ ስድስት ፡ ሺ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

ብንያምም ፡ በኵሩን ፡ ቤላን ፥ ሁለተኛውንም ፡ ፩
አስቤልን ፥ ሦስተኛውንም ፡ አሐራን ፥ አራተ ፪
ኛውንም ፡ ኖሐን ፥ አምስተኛውንም ፡ ራፋን ፡
ወለደ ። ለቤላም ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ፤ አዳር ፥ ፫
ጌራ ፥ አቢሁድ ፥ አቢሱ ፥ ናዕማን ፥ አሖዋ ፥ ፬
ጌራ ፥ ሰፉፋም ፥ ሑራም ። እነዚህም ፡ የኤ ፭ ፮
ሁድ ፡ ልጆች ፡ ናቸው ፤ እነዚህ ፡ በጌባ ፡ የሚቀ
መጡ ፡ የአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ናቸው ፤
ወደ ፡ መናሐትም ፡ ተማረኩ ፤ ናዕማን ፥ አኪያ ፥ ፯
ጌራ ፥ እነርሱም ፡ ተማረኩ ። ዖዛንና ፡ አሒሑ
ድን ፡ ወለደ ። ሸሐራይምም ፡ ሚስቶቹን ፡ ሑሺ ፰
ምንና ፡ በዕራን ፡ ከሰደደ ፡ በኋላ ፡ በሞዓብ ፡ ሜዳ ፡

፱ ልጆች ፡ ወለደ ። ከሚስቱ ፡ ከሖዴሽ ፡ ዮባብን ፥ ፲ ዲብያን ፥ ማሴን ፥ ማልካምን ፥ ይዑጽን ፥ ሻክያን ፥ ሚርማን ፡ ወለደ ። እነዚህም ፡ ልጆች ፡ ፲፩ የአባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ። ከሑሺም ፡ አቢጡብንና ፡ ኤልፍዓልን ፡ ወለደ ። ፲፪ የኤልፍዓልም ፡ ልጆች ፤ ዔቤር ፥ ሚሻም ፥ አናንና ፡ ሎድን ፡ መንደሮቻቸውንም ፡ የሠራ ፡ ፲፫ ሻሚድ ፤ በሪዓ ፥ ሽማዕ ፡ የጌትን ፡ ሰዎች ፡ ያሳደዱ ፡ የኤሎን ፡ ሰዎች ፡ የአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ ፲፬ አለቆች ፡ ነበሩ ፤ አሒዮ ፥ ሻሻቅ ፥ ይሬምት ፥ ፲፭ ፲፮ ዝባድያ ፥ ዓራድ ፥ ዔድር ፥ ሚካኤል ፥ ይሽጳ ፥ ፲፯ ዮሐ ፥ የበሪዓ ፡ ልጆች ፤ ዝባድያ ፥ ሚሱላም ፥ ፲፰ ሕዝቂ ፥ ሔቤር ፥ ይሽምራይ ፥ ይዝሊያ ፥ ዮባብ ፥ ፲፱ የኤልፍዓል ፡ ልጆች ፤ ያቂም ፥ ዝክሪ ፥ ዘብዲ ፥ ፳ ፳፩ ኤሊዔናይ ፥ ጺልታይ ፥ ኤሊኤል ፥ ዓዳያ ፥ ብራያ ፥ ሺምራት ፥ የሰሜኢ ፡ ልጆች ፤ ፳፪ ይሽጳን ፥ ዔቤር ፥ ኤሊኤል ፥ ፳፫ ዓብዶን ፥ ዝክሪ ፥ ፳፬ ፳፭ ሐናን ፥ ሐናንያ ፥ ኤላም ፥ ዓንቶትያ ፥ ይፍዴያ ፥ ፋኑኤል ፥ የሰሴቅ ፡ ልጆች ፤ ፳፮ ሽምሽራይ ፥ ፳፯ ሽሃሪያ ፥ ጎቶልያ ፥ ያሬሽያ ፥ ኤልያስ ፥ ዝክሪ ፥ ፳፰ የይሮሐም ፡ ልጆች ። እነዚህ ፡ በትውልዶቻቸው ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ፤ የአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ፤ እነዚህ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተቀመጡ ።

፳፱ የሚስቱ ፡ ስም ፡ መዓካ ፡ የነበረው ፡ የገባዖን ፡ ፴ አባት ፡ ይዒኤል ፥ የበኵር ፡ ልጁ ፡ ዓብዶን ፥ ፴፩ ጹር ፥ ቂስ ፥ በኣል ፥ ናዳብ ፥ ጌዶር ፥ አሒዮ ፥ ፴፪ ዘኩር ፡ በገባዖን ፡ ተቀመጡ ። ሚቅሎት ፡ ሰምአን ፡ ወለደ ፤ እነርሱ ፡ ደግሞ ፡ ከወንድሞቻቸው ፡ ጋር ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በወንድሞቻቸው ፡ ፴፫ ፊት ፡ ለፊት ፡ ተቀመጡ ። ኔር ፡ ቂስን ፡ ወለደ ፤ ቂስም ፡ ሳኦልን ፡ ወለደ ፤ ሳኦልም ፡ ዮናታንን ፥ ሚልኪሳን ፥ አሚናዳብን ፥ አስበኣልን ፡ ፴፬ ወለደ ። የዮናታንም ፡ ልጅ ፡ መሪበኣል ፡ ነበረ ፤ ፴፭ መሪበኣልም ፡ ሚካን ፡ ወለደ ። የሚካም ፡ ልጆች ፡ ፒቶን ፥ ሜሌክ ፥ ታሬዓ ፥ አካዝ ፡ ነበሩ ። ፴፮ አካዝም ፡ ይሆዓዳን ፡ ወለደ ፤ ይሆዓዳም ፡ ዓሌሜትን ፥ ዓዝሞትን ፥ ዘምሪን ፡ ወለደ ፤ ዘም ፴፯ ሪም ፡ ሞጻን ፡ ወለደ ። ሞጻም ፡ ቢንዓን ፡ ወለደ ፤ ልጁም ፡ ረፋያ ፡ ነበረ ፥ ልጁ ፡ ኤልዓሣ ፥ ልጁ ፡ ፴፰ ኤሴል ፤ ለኤሴልም ፡ ስድስት ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ፤ ስማቸውም ፡ ይህ ፡ ነበረ ፤ ዓዝሪቃም ፥ በክሩ ፥ እስማኤል ፥ ሽዓርያ ፥ አብድዩ ፥ ሐናን ፤ ፴፱ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የኤሴል ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ። የወንድሙም ፡ የኤሴል ፡ ልጆች ፤ በኵሩ ፡ ኡላም ፥ ሁለተኛውም ፡ ኢያስ ፥ ሦስተኛውም ፡ ኤሊፋ ፵ ላት ። የኡላም ፡ ልጆች ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላንና ፡ ቀስተኞች ፡ ነበሩ ፤ ለእነርሱም ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ የሚያህሉ ፡ ብዙ ፡ ልጆችና ፡ የልጅ ፡ ልጆች ፡ ነበሩአቸው ፤ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የብንያም ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ በየትውልዳቸው ፡ ተቈጠሩ ፤ እነሆም ፥ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፈዋል ። ይሁዳም ፡ ስለ ፡ ኃጢአታቸው ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ተማረኩ ። ፪ በአውራጃዎቻቸውና ፡ በከተሞቻቸው ፡ መጀመሪያ ፡ የተቀመጡ ፡ እስራኤልና ፡ ካህናት ፡ ሌዋውያንም ፡ ናታኒምም ፡ ነበሩ ። ፫ ከይሁዳ ፡ ልጆችና ፡ ከብንያም ፡ ልጆች ፡ ከኤፍሬምና ፡ ከምናሴ ፡ ልጆች ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተቀመጡ ። ፬ ከይሁዳ ፡ ልጅ ፡ ከፋሬስ ፡ ልጆች ፡ የባኒ ፡ ልጅ ፡ የኦምሪ ፡ ልጅ ፡ የዖምሪ ፡ ልጅ ፡ የዓሚሁድ ፡ ልጅ ፡ ዑታይ ፡ ደግሞ ፡ ተቀመጠ ። ፭ ከሴሎናውያንም ፡ በኵሩ ፡ ዓሣያና ፡ ልጆቹ ። ፮ ከዛራም ፡ ልጆች ፡ ይዑኤልና ፡ ወንድሞቻቸው ፥ ስድስት ፡ መቶ ፡ ዘጠና ። ፯ ከብንያምም ፡ ልጆች ፡ የሐስኑአ ፡ ልጅ ፡ የሆዳይዋ ፡ ልጅ ፡ የሚሱላም ፡ ልጅ ፡ ሰሉ ፤ ፰ የይሮሐም ፡ ልጅ ፡ ብኔያ ፤ የሚክሪ ፡ ልጅ ፡ የኦዚ ፡ ልጅ ፡ ኤላ ፤ የይብንያ ፡ ልጅ ፡ የራጉኤል ፡ ልጅ ፡ የሰፋጥያስ ፡ ልጅ ፡ ሚሱላም ፤ ፱ በየትውልዳቸውም ፡ ወንድሞቻቸው ፡ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ስድስት ፡ ነበሩ ፤ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ የአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ።

፲ ከካህናቱም ፡ ዮዳኤ ፥ ዮአሪብ ፥ ያኪን ፤ ፲፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ የአኪጡብ ፡ ልጅ ፡ የመራዮት ፡ ልጅ ፡ የሳዶቅ ፡ ልጅ ፡ የሚሱላም ፡ ልጅ ፡ የኬልቅያስ ፡ ልጅ ፡ ዓዛርያስ ፤ ፲፪ የመልክያ ፡ ልጅ ፡ የጳስኮር ፡ ልጅ ፡ የይሮሐም ፡ ልጅ ፡ ዓዳያ ፤ የኢሜር ፡ ልጅ ፡ የምሺላሚት ፡ ልጅ ፡ የሚሱላም ፡ ልጅ ፡ የየሕዜራ ፡ ልጅ ፡ የዓዲኤል ፡ ልጅ ፡ መዕሣይ ፤ ፲፫ የአባቶቻቸውም ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ወንድሞቻቸው ፡ ሺህ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ ነበሩ ፤ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ማገልገል ፡ ሥራ ፡ እጅግ ፡ ብልሃተኞች ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ።

፲፬ ከሌዋውያንም ፡ የሜራሪ ፡ ልጆች ፡ የአሳብያ ፡ ልጅ ፡ የዓዝሪቃም ፡ ልጅ ፡ የአሱብ ፡ ልጅ ፡ ሸማያ ፤ ፲፭ በቅበቃር ፥ ኤሬስ ፥ ጋላል ፥ የአሳፍ ፡ ልጅ ፡ የዝክሪ ፡ ልጅ ፡ የሚካ ፡ ልጅ ፡ መታንያ ፤ ፲፮ የኤዶታም ፡ ልጅ ፡ የጋላል ፡ ልጅ ፡ የሰሙስ ፡ ልጅ ፡ አብድያ ፤ በነጦፋውያንም ፡ መንደሮች ፡ የተቀመጠው ፡ የሕልቃና ፡ ልጅ ፡ የአሳ ፡ ልጅ ፡ በራክያ ።

፲፯ በረኞችም ፡ ሰሎም ፥ ዓቁብ ፥ ጤልሞን ፥ አሒማን ፥ ወንድሞቻቸውም ፡ ነበሩ ፤ ሰሎምም ፡ አለቃ ፡ ነበረ ። ፲፰ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ በንጉሥ ፡ በር ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ነበሩ ፤ ለሌዊ ፡ ልጆች ፡ ሰፈር ፡ በረኞች ፡ ነበሩ ። ፲፱ የቆሬም ፡ ልጅ ፡ የአብያሳፍ ፡ ልጅ ፡ የቆሬ ፡ ልጅ ፡ ሰሎም ፡ ከአባቱም ፡ ቤት ፡ የነበሩ ፡ ወንድሞቹ ፡ ቆሬያው

ያን ፡ በማገልገል ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ ነበሩ ፥ የድን
ኳኑንም ፡ መድረክ ፡ ይጠብቁ ፡ ነበር ። አባቶቻ
ቸውም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሰፈር ፡ መግቢያ ፡
፳፤ ጠብቀው ፡ ነበር ። አስቀድሞም ፡ የአልዓዛር ፡
ልጅ ፡ ፊንሐስ ፡ አለቃቸው ፡ ነበረ ፤ እግዚአብ
፳፩፤ ሔርም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረ ። የሜሱላም ፡
ልጅ ፡ ዘካርያስ ፡ የመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ደጅ ፡
፳፪፤ በረኛ ፡ ነበረ ። የመድረኩ ፡ በረኞች ፡ ይሆኑ ፡
ዘንድ ፡ የተመረጡ ፡ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ሁለት ፡
መቶ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ነበሩ ። ዳዊትና ፡ ነቢዩ ፡
ሳሙኤል ፡ በሥራቸው ፡ ያቆሙአቸው ፡ እነ
ዚህ ፡ በመንደሮቻቸው ፡ በየትውልዳቸው ፡ ተቈ
፳፫፤ ጠሩ ። እነርሱና ፡ ልጆቻቸውም ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ቤት ፡ በድንኳኑ ፡ ደጆች ፡ ላይ ፡ ዘበኞች ፡
፳፬፤ ነበሩ ። በአራቱ ፡ ማዕዘኖች ፥ በምሥራቅ ፥ በም
ዕራብ ፥ በሰሜን ፥ በደቡብ ፥ በረኞች ፡ ነበሩ ።
፳፭፤ ወንድሞቻቸውም ፡ በመንደሮቻቸው ፡ ሆነው ፥
በየሰባትም ፡ ቀን ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ሊሆኑ ፡
፳፮፤ ከጊዜ ፡ ወደ ፡ ጊዜ ፡ ይገቡ ፡ ነበር ። ከሌዋውያ
ንም ፡ የነበሩ ፡ አራቱ ፡ የበረኞች ፡ አለቆች ፡
ዘወትር ፡ በሥራቸው ፡ ይቀመጡ ፡ ነበር ፤ በእግዚ
አብሔርም ፡ ቤት ፡ ባሉ ፡ ጓዳዎችና ፡ ቤት ፡ መዛ
፳፯፤ ግብት ፡ ላይ ፡ ነበሩ ። የእግዚአብሔርንም ፡
ቤት ፡ የሚጠብቁ ፥ ጥዋት ፡ ጥዋትም ፡ ደጆቹን ፡
የሚከፍቱ ፡ እነርሱ ፡ ነበሩና ፡ በዚያ ፡ ያድሩ ፡
ነበር ።
፳፰፤ ዕቃውም ፡ በቍጥር ፡ ይገባና ፡ ይወጣ ፡ ነበ
ርና ፡ ከእነዚህ ፡ አንዳንዱ ፡ በማገልገያው ፡
፳፱፤ ዕቃ ፡ ላይ ፡ ሹሞች ፡ ነበሩ ። ከእነርሱም ፡ አን
ዳንዶቹ ፡ በመቅደሱ ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ በመልካ
ሙም ፡ ዱቄት ፥ በወይን ፡ ጠጅም ፥ በዘይቱም ፥
በዕጣኑም ፥ በሽቱውም ፡ ላይ ፡ ሹሞች ፡ ነበሩ ።
፴፤ ከካህናቱም ፡ ልጆች ፡ አንዳንዶቹ ፡ የሽቱውን ፡
፴፩፤ ቅባት ፡ ያጣፍጡ ፡ ነበር ። የቆሬያዊውም ፡ የሰ
ሎም ፡ በኵር ፡ ሌዋዊው ፡ ማቲትያ ፡ በምጣድ ፡
፴፪፤ በሚጋገረው ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ ሹም ፡ ነበረ ። በየሰ
ንበቱም ፡ ያዘጋጁ ፡ ዘንድ ፡ ከወንድሞቻቸው ፡
ከቀዓታውያን ፡ አንዳንዱ ፡ በገጹ ፡ ኅብስት ፡ ላይ ፡
ሹሞች ፡ ነበሩ ።
፴፫፤ ከሌዋውያንም ፡ ወገን ፡ የአባቶቻቸው ፡
ቤቶች ፡ አለቆች ፡ የነበሩ ፡ መዘምራን ፡ እነዚህ ፡
ናቸው ፤ ሥራቸውም ፡ ሌሊትና ፡ ቀን ፡ ነበረና ፡
ያለ ፡ ሌላ ፡ ሥራ ፡ በየጓዳቸው ፡ ይቀመጡ ፡
፴፬፤ ነበር ። እነዚህ ፡ ከሌዋውያን ፡ የአባቶቻቸው ፡
ቤቶች ፡ አለቆች ፡ በየትውልዳቸው ፡ አለቆች ፡
ነበሩ ። እነዚህም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ይቀመጡ ፡
ነበር ።
፴፭፤ የሚስቱ ፡ ስም ፡ መዓካ ፡ የነበረው ፡ የገባዖን ፡
፴፮፤ አባት ፡ ይዒኤል ፥ የበኵር ፡ ልጁም ፡ ዓብዶን ፥
፴፯፤ ጹር ፥ ቂስ ፥ በአል ፥ ኔር ፥ ናዳብ ፥ ጌዶር ፥
አሒዮ ፥ ዘኩር ፥ ሚቅሎት ፥ በገባዖን ፡ ይቀ
፴፰፤ መጡ ፡ ነበር ። ሚቅሎትም ፡ ሳምአን ፡ ወለደ ፤
እነርሱ ፡ ደግሞ ፡ ከወንድሞቻቸው ፡ ጋር ፡ በኢ
የሩሳሌም ፡ በወንድሞቻቸው ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡
ይቀመጡ ፡ ነበር ። ኔርም ፡ ቂስን ፡ ወለደ ፤ ፴፱፤
ቂስም ፡ ሳኦልን ፡ ወለደ ፤ ሳኦልም ፡ ዮናታንን ፥
ሜልኪሳን ፥ አሚናዳብን ፥ አስበኣልን ፡ ወለደ ።
፵፤ የዮናታንም ፡ ልጅ ፡ መሪበኣል ፡ ነበረ ፤ መሪበ
፵፩፤ ኣልም ፡ ሚካን ፡ ወለደ ። የሚካም ፡ ልጆች ፡
፵፪፤ ፒቶን ፥ ሜሌክ ፥ ታሬዓ ፥ አካዝ ፡ ነበሩ ። አካ
ዝም ፡ የዕራን ፡ ወለደ ፤ የዕራም ፡ ዓሌሜትን ፥
ዓዝሞትን ፥ ዘምሪን ፡ ወለደ ፤ ዘምሪም ፡ ሞጻን ፡
፵፫፤ ወለደ ። ሞጻም ፡ ቢንዓን ፡ ወለደ ፥ ልጁም ፡
ረፋያ ፡ ነበረ ፥ ልጁ ፡ ኤልዓሣ ፥ ልጁ ፡ ኤሴል ፤
፵፬፤ ለኤሴልም ፡ ስድስት ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ፤ ስማ
ቸውም ፡ ይህ ፡ ነበረ ፤ ዓዝሪቃም ፥ በክሩ ፥
እስማኤል ፥ ሸዓርያ ፥ አብድዩ ፥ ሐናን ፤ እነዚህ ፡
የኤሴል ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ከእስራኤል ፡ ጋር ፡
ተዋጉ ፤ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ከፍልስጥኤማ
ውያን ፡ ፊት ፡ ሸሹ ፥ ተወግተውም ፡ በጊልቦዓ ፡
፪፤ ተራራ ፡ ላይ ፡ ወደቁ ። ፍልስጥኤማውያንም ፡
ሳኦልንና ፡ ልጆቹን ፡ በእግር ፡ በእግራቸው ፡
ተከትለው ፡ አበረሩአቸው ፤ ፍልስጥኤማውያ
ንም ፡ የሳኦልን ፡ ልጆች ፡ ዮናታንንና ፡ አሚና
፫፤ ዳብን ፡ ሜልኪሳንም ፡ ገደሉ ። ሰልፍም ፡ በሳ
ኦል ፡ ላይ ፡ ጠነከረ ፥ ቀስተኞችም ፡ አገኙት ፤
፬፤ ከቀስተኞቹም ፡ የተነሣ ፡ ተጨነቀ ። ሳኦልም ፡
ጋሻ ፡ ጃግሬውን ፦ እነዚህ ፡ ቈላፋን ፡ መጥ
ተው ፡ እንዳይዘብቱብኝ ፡ ሰይፍህን ፡ መዝ
ዘህ ፡ ውጋኝ ፡ አለው ። ጋሻ ፡ ጃግሬው ፡ ግን ፡
እጅግ ፡ ፈርቶ ፡ ነበርና ፡ እንቢ ፡ አለ ። ሳኦልም ፡
፭፤ ሰይፉን ፡ ወስዶ ፡ በላዩ ፡ ወደቀ ። ጋሻ ፡ ጃግሬ
ውም ፡ ሳኦል ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡
፮፤ ደግሞ ፡ በሰይፉ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ሞተ ። ሳኦ
ልና ፡ ሦስቱም ፡ ልጆቹ ፡ የቤቱም ፡ ሰዎች ፡
ሁሉ ፡ በአንድ ፡ ላይ ፡ ሞቱ ።
፯፤ በሸለቆውም ፡ የነበሩት ፡ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡
ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሸሹ ፥ ሳኦልና ፡ ልጆቹም ፡ እንደ
ሞቱ ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ ከተሞቻቸውን ፡ ለቀቀው ፡ ሸሹ ፤
ፍልስጥኤማውያንም ፡ መጥተው ፡ ተቀመጡብ
፰፤ ቸው ። በነጋውም ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ የሞ
ቱትን ፡ ለመግፈፍ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ሳኦልንና ፡
ልጆቹን ፡ በጊልቦዓ ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ወድቀው ፡
፱፤ አገኙአቸው ። ገፈፉትም ፥ ራሱንና ፡ መሣሪያ
ውንም ፡ አንሥተው ፡ ለጣዖቶቻቸውና ፡ ለሕ
ዝቡ ፡ የምስራች ፡ ይወስዱ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ፍልስ
፲፤ ጥኤማውያን ፡ አገር ፡ ዙሪያ ፡ ሰደዱ ። መሣሪያ
ውንም ፡ በአምላኮቻቸው ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ አኖሩ ፤
ራሱንም ፡ በዳጎን ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ቸነከሩት ።
፲፩፤ የኢያቢስ ፡ ገለዓድም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ፍልስጥ
ኤማውያን ፡ በሳኦል ፡ ላይ ፡ ያደረጉትን ፡ ሁሉ ፡
፲፪፤ በሰሙ ፡ ጊዜ ፥ ጽኑዓን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ተነ
ሥተው ፡ የሳኦልን ፡ሬሳ ፡ የልጆቹንም ፡ ሬሳ ፡
ወሰዱ ፥ ወደ ፡ ኢያቢስም ፡ አመጡአቸው ፤ በኢ
ያቢስም ፡ ካለው ፡ ከትልቁ ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ አጥ

ንቶቻቸውን ፡ ቀበሩ ፥ ሰባት ፡ ቀንም ፡ ጾሙ ።

፲፫ እንዲሁ ፡ ሳኦል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ስላ ደረገው ፡ ኃጢአት ፥ የእግዚአብሔርንም ፡ ቃል ፡ ስላልጠበቀ ፡ ሞተ ። ደግሞም ፡ መናፍስት ፡ ፲፬ ጠሪ ፡ ስለ ፡ ጠየቀ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ስላል ጠየቀ ፥ ስለዚህ ፡ ገደለው ፥ መንግሥቱንም ፡ ወደ ፡ እሴይ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ አሳለፈው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ በኬብሮን ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ተሰብስበው ፡— እነሆ ፥ እኛ ፡ የአጥንትህ ፡ ፪ ፍላጭ ፡ የሥጋህ ፡ ቍራጭ ፡ ነን ፤ አስቀድሞ ፡ ሳኦል ፡ ንጉሥ ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ እስራኤልን ፡ የም ታወጣና ፡ የምታገባ ፡ አንተ ፡ ነበርህ ፤ አምላ ክህ ፡ እግዚአብሔርም ፡— ሕዝቤን ፡ እስራኤ ልን ፡ አንተ ፡ ትጠብቃለህ ፤ በሕዝቤም ፡ በእስ ራኤል ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ ትሆናለህ ፡ ብሎህ ፡ ነበር ፡ ፫ አሉት ። የእስራኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ መጡ ፤ ዳዊ ትም ፡ በኬብሮን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ አደረገ ፤ በሳሙኤልም ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ዳዊትን ፡ ቀቡት ።

፬ ዳዊትም ፡ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ኢያቡስ ፡ ወደምትባል ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሄዱ ፤ በአገ ሩም ፡ የተቀመጡ ፡ ኢያቡሳውያን ፡ በዚያ ፡ ፭ ነበሩ ። በኢያቡስም ፡ የተቀመጡ ፡ ዳዊትን ፡— ወደዚህ ፡ አትገባም ፡ አሉት ፤ ዳዊት ፡ ግን ፡ አምባይቱን ፡ ጽዮንን ፡ ያዘ ፤ እርስዋም ፡ የዳ ፮ ዊት ፡ ከተማ ፡ ናት ። ዳዊትም ፡— ኢያቡሳው ያንን ፡ አስቀድሞ ፡ የሚመታ ፡ ሰው ፡ አለቃና ፡ መኰንን ፡ ይሆናል ፡ አለ ። የጽሩያም ፡ ልጅ ፡ ኢዮአብ ፡ አስቀድሞ ፡ ወጣ ፥ አለቃም ፡ ሆነ ። ፯ ዳዊትም ፡ በአምባይቱ ፡ ውስጥ ፡ ተቀመጠ ፤ ስለዚህም ፡ የዳዊት ፡ ከተማ ፡ ብለው ፡ ጠሩአት ። ፰ ከሚሎም ፡ጀምሮ ፡ በዙሪያው ፡ ከተማ ፡ ሠራ ፤ ኢዮአብም ፡ የቀረውን ፡ ከተማ ፡ አበጀ ። ፱ ዳዊትም ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረና ፡ እየበረታ ፡ ሄደ ።

፲ ለዳዊትም ፡ የነበሩት ፡ የኃያላን ፡ አለቆች ፡ እነ ዚህ ፡ ናቸው ፤ ስለ ፡ እስራኤል ፡ እንደ ፡ ተናገ ረው ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ያነግሡት ፡ ዘንድ ፡ ከእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ በመንግሥቱ ፡ ፲፩ ላይ ፡ አጸኑት ። የዳዊትም ፡ ኃያላን ፡ ቍጥር ፡ ይህ ፡ ነበረ ፤ የሠላሳው ፡ አለቃ ፡ የሐክሞናዊው ፡ ልጅ ፡ ያሾብዓም ፡ ነበረ ፤ እርሱ ፡ ጦሩን ፡ አን ሥቶ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሰው ፡ በአንድ ፡ ጊዜ ፡ ፲፪ ገደለ ። ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ በሦስቱ ፡ ኃያላን ፡ መካከል ፡ የነበረ ፡ የአሆሃዊው ፡ የዱዲ ፡ ልጅ ፡ ፲፫ አልዓዛር ፡ ነበረ ። እርሱ ፡ ከዳዊት ፡ ጋር ፡ በፈ ስደሚም ፡ ነበረ ፥ በዚያም ፡ ገብስ ፡ በሞላበት ፡ እርሻ ፡ ውስጥ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ለሰልፍ ፡ ተሰብስበው ፡ ነበር ፤ ሕዝቡም ፡ ከፍልስጥኤማ ውያን ፡ ፊት ፡ ሸሹ ። በእርሻውም ፡ መካከል ፡ ፲፬ ቆመው ፡ ጠበቁት ፥ ፍልስጥኤማውያንንም ፡ ገደሉ ፤ እግዚአብሔርም ፡ በታላቅ ፡ ማዳን ፡ አዳናቸው ።

፲፭ ከሠላሳውም ፡ አለቆች ፡ ሦስቱ ፡ ወርደው ፡ ዳዊት ፡ ወዳለበት ፡ ወደ ፡ ዓለቱ ፡ ወደ ፡ ዓዶላም ፡ ዋሻ ፡ መጡ ፤ የፍልስጥኤማውያንም ፡ ጭፍራ ፡ ፲፮ በራፋይም ፡ ሸለቆ ፡ ሰፍሮ ፡ ነበር ። በዚያም ፡ ጊዜ ፡ ዳዊት ፡ በምሽጉ ፡ ውስጥ ፡ ነበረ ፥ የፍል ስጥኤማውያንም ፡ ጭፍራ ፡ በቤተ ፡ ልሔም ፡ ፲፯ ነበረ ። ዳዊትም ፡— በበሩ ፡ አጠገብ ፡ ካለችው ፡ ከቤተ ፡ ልሔም ፡ ምንጭ ፡ ውኃ ፡ ማን ፡ ይሰጠ ፲፰ ኛል ? ብሎ ፡ ተመኘ ። እነዚህም ፡ ሦስቱ ፡ የፍ ልስጥኤማውያንን ፡ ሠራዊት ፡ ቀድደው ፡ ሄዱ ፥ በበሩም ፡ አጠገብ ፡ ካለችው ፡ ከቤተ ፡ ልሔም ፡ ምንጭ ፡ ውኃ ፡ ቀዱ ፤ ይዘውም ፡ ለዳዊት ፡ አመጡለት ። እርሱ ፡ ግን ፡ ሊጠጣ ፡ አልወደ ደም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አፍስሶ ፡— ፲፱ ይህን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ አምላኬ ፡ ይከልክለኝ ፤ በነፍሳቸው ፡ የደፈሩትን ፡ የእነዚህን ፡ ሰዎች ፡ ደም ፡ እጠጣለሁን ? በነፍሳቸው ፡ አምጥተው ታል ፡ አለ ። ስለዚህም ፡ ይጠጣ ፡ ዘንድ ፡ አል ወደደም ። ሦስቱም ፡ ኃያላን ፡ ያደረጉት ፡ ይህ ፡ ነው ።

፳ የኢዮአብም ፡ ወንድም ፡ አቢሳ ፡ የሦስቱ ፡ አለቃ ፡ ነበረ ፤ ጦሩንም ፡ በሦስት ፡ መቶ ፡ ላይ ፡ አንሥቶ ፡ ገደላቸው ፥ በሦስቱም ፡ መካከል ፡ ፳፩ ስሙ ፡ የተጠራ ፡ ነበረ ። በሁለተኛውም ፡ ተራ ፡ በሆኑት ፡ በሦስቱ ፡ መካከል ፡ የከበረ ፡ ነበረ ፥ አለ ቃቸውም ፡ ሆነ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ፊተኞቹ ፡ ወደ ፡ ሦስቱ ፡ አልደረሰም ።

፳፪ በቀብስኤልም ፡ የነበረው ፥ ታላቅ ፡ ሥራ ፡ ያደረገው ፡ የጽኑዕ ፡ ሰው ፡ የዮዳሄ ፡ ልጅ ፡ በና ያስ ፡ የሞዓባዊን ፡ የአሪኤልን ፡ ሁለቱን ፡ ልጆች ፡ ገደለ ፤ በአመዳይም ፡ ወራት ፡ ወርዶ ፡ በጕድ ፳፫ ጓድ ፡ ውስጥ ፡ አንበሳ ፡ ገደለ ። ቁመቱም ፡ አም ስት ፡ ክንድ ፡ የነበረውን ፡ ረጅሙን ፡ ግብጻዊ ውን ፡ ሰው ፡ ገደለ ፤ በግብጻዊውም ፡ እጅ ፡ የሸ ማኔ ፡ መጠቅለያ ፡ የመሰለ ፡ ጦር ፡ ነበረ ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ በትር ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ወረደ ፥ ከግብ ጻዊውም ፡ እጅ ፡ ጦሩን ፡ ነቅሎ ፡ በገዛ ፡ ጦሩ ፡ ፳፬ ገደለው ። የዮዳሄ ፡ ልጅ ፡ በናያስ ፡ ያደረገው ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ስሙም ፡ በሦስቱ ፡ ኃያላን ፡ መካከል ፡ ፳፭ የተጠራ ፡ ነበረ ። እነሆ ፥ ከሠላሳው ፡ ይልቅ ፡ የከበረ ፡ ነበረ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ፊተኞቹ ፡ ወደ ፡ ሦስቱ ፡ አልደረሰም ። ዳዊትም ፡ በዘበ ኞቹ ፡ ላይ ፡ ሾመው ።

፳፮ ደግሞም ፡ በጭፍሮች ፡ ዘንድ ፡ የነበሩት ፡ ኃያላን ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ የኢዮአብ ፡ ወንድም ፡ አሣሄል ፥ የቤተ ፡ ልሔሙ ፡ ሰው ፡ የዱዲ ፡ ልጅ ፡ ፳፯ ኤልያናን ፥ ሃሮራዊው ፡ ሳሞት ፥ ፈሎናዊው ፡ ፳፰ ሴሌስ ፥ የቴቁሔ ፡ ሰው ፡ የዒስካ ፡ ልጅ ፡ ዒራስ ፥ ፳፱ ዓናቶታዊው ፡ አቢዔዜር ፥ ኩሳታዊው ፡ ሴቤ ፴ ካይ ፥ አሆሃዊው ፡ ዔላይ ፥ ነጦፋዊው ፡ ሞኤሬ ፥

፴፩፤ የነጦፋዊው ፡ የበዓና ፡ ልጅ ፡ ሔሌድ ÷ ከብን
ያም ፡ ወገን ፡ ከጊብዓ ፡ የሪባይ ፡ ልጅ ፡ ኤታይ ÷
፴፪፤ ጲርዓቶናዊው ፡ በናያስ ÷ የገዓስ ፡ ወንዝ ፡ ሰው ፡
፴፫፤ ኡሪ ÷ ዓረባዊው ፡ አቢኤል ÷ ባሑሩማዊው ፡
፴፬፤ ዓዝሞት ÷ ሰዓልቦናዊው ፡ ኤሊያሕባ ÷ የጊዞና
ዊው ፡ የአሳን ፡ ልጆች ÷ የሃራራዊው ፡ የሻጌ ፡
፴፭፤ ልጅ ፡ ዮናታን ÷ የአሮዳዊው ፡ የአራር ፡ ልጅ ፡
፴፮፤ አምናን ÷ የኡር ፡ ልጅ ፡ ኤሊፋል ÷ ምኬራታ
፴፯፤ ዊው ፡ አፌር ÷ ፍሎናዊው ፡ አኪያ ÷ ቀርሜ
ሎሳዊው ፡ ሐጽሮ ÷ የኤዝባይ ፡ ልጅ ፡ ነዕራይ ÷
፴፰፤ የናታንም ፡ ወንድም ፡ ኢዮኤል ÷ የሃግሪ ፡
፴፱፤ ልጅ ፡ ሚብሐር ÷ አሞናዊው ፡ ጼሌቅ ÷ የጽ
ሩያ ፡ ልጅ ፡ የኢዮአብ ፡ ጋሻ ፡ ጃግሬ ፡ ቤሮታ
፵፤ ዊው ፡ ነሃራይ ÷ ይትራዊው ፡ ዒራስ ÷ ይትራ
፵፩፤ ዊው ፡ ጋሬብ ÷ ኬጢያዊው ፡ ኦርዮ ÷ የአሕ
፵፪፤ ላይ ፡ ልጅ ፡ ዛባድ ÷ የሮቤላዊው ፡ የሺዛ ፡ ልጅ ፡
ዓዲና ÷ እርሱ ፡ የሮቤላውያን ፡ አለቃ ፡ ነበረ ÷
፵፫፤ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ሠላሳ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ÷ የማ
ዕካ ፡ ልጅ ፡ ሐናን ÷ ሚትናዊው ፡ ኢዮሣፍጥ ÷
፵፬፤ አስታሮታዊው ፡ ዖዝያ ÷ የአሮዔራዊው ፡ የኮ
፵፭፤ ታም ፡ ልጆች ፡ ሻማና ፡ ይዒኤል ÷ የሺምሪ ፡
ልጅ ፡ ይዲኤል ÷ ወንድሙም ፡ ቲጻዊው ፡ ዮሐ ÷
፵፮፤ መሐዋዊው ፡ ኤሊኤል ÷ ይሪባይ ÷ ዮሻውያ ÷
የኤልነዓም ፡ ልጆች ÷ ሞዓባዊው ፡ ይትማ ÷
፵፯፤ ኤሊኤል ÷ ዖቤድ ÷ ምጸባዊው ፡ የዕሢኤል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩፤ በጺቅላግም ፡ ከቂስ ፡ ልጅ ፡ ከሳኦል ፡ በተሸ
ሸገ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ የመጡ ፡ እነዚህ ፡
ናቸው ፤ በሰልፍም ፡ በገዙት ፡ ኃያላን ፡ መካ
፪፤ ከል ፡ ነበሩ ። ቀስተኞችም ፡ ነበሩ ÷ በቀኝና ፡
በግራም ፡ እጃቸው ፡ ድንጋይ ፡ ሊወነጭፉ ፡
ፍላጻም ፡ ሊወረውሩ ፡ ይችሉ ፡ ነበር ፤ ከብን
፫፤ ያም ፡ ወገን ፡ የሳኦል ፡ ወንድሞች ፡ ነበሩ ። አለ
ቃቸው ፡ አሒዔዝር ፡ ነበረ ÷ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡
ኢዮአስ ÷ የጊብዓዊው ፡ የሸማዓ ፡ ልጆች ፤ ይዝ
ኤል ÷ ፋሌጥ ÷ የዓዝሞት ፡ ልጆች ፤ በራኪያ ÷
፬፤ ዓናቶታዊው ፡ ኢዩ ÷ ገባዖናዊው ፡ ሰማያስ ÷
እርሱ ፡ በሠላሳው ፡ መካከልና ፡ በሠላሳው ፡ ላይ ፡
ኃያል ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ኤርምያስ ÷ የሕዚኤል ÷
፭፤ ዮሐናን ÷ ገድሮታዊ ፡ ዮዛባት ÷ ኤሉዛይ ÷ ኢያ
ሪሙት ÷ በዓልያ ÷ ሰማራያ ÷ ሐሩፋዊው ፡ ሰፋ
፮፤ ጥያስ ÷ ቆሬያውያን ፡ ሕልቃና ÷ ይሺያ ÷ ዓዛ
፯፤ ርኤል ÷ ዮዛር ÷ ያሾብዓም ፤ የጌዶር ፡ ሰው ፡
የይሮሐም ፡ ልጆች ፡ ዮዔላ ÷ ዝባድያ ።
፰፤ ዳዊትም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ውስጥ ፡ ባለችው ፡
በአምባይቱ ፡ ሳለ ፡ ከጋድ ፡ ወገን ፡ የሆኑ ፡ እነ
ዚህ ፡ ጋሻና ፡ ጦር ፡ የሚይዙ ÷ ጽኑዓን ፡ ኃያ
ላን ÷ ሰልፈኞች ÷ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተጠጉ ፤ ፊታ
ቸውም ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ፊት ፡ ነበረ ÷ በተራ
ራም ፡ ላይ ፡ እንደሚዘልል ፡ ሚዳቋ ፡ ፈጣኖች ፡
፱፤ ነበሩ ። አለቃው ፡ ዔጼር ÷ ሁለተኛው ፡ አብ
፲፤ ድዩ ÷ ሦስተኛው ፡ ኤልያብ ÷ አራተኛው ፡ መስ
፲፩፤ መና ÷ አምስተኛው ፡ ኤርምያስ ÷ ስድስተኛው ፡
፲፪፤ ዓታይ ÷ ሰባተኛው ፡ ኤሊኤል ÷ ስምንተኛው ፡
፲፫፤ ዮሐናን ÷ ዘጠኘኛው ፡ ኤልዛባድ ÷ አሥረኛው ፡
ኤርምያስ ÷ አሥራ ፡ አንደኛው ፡ መክበናይ ።
፲፬፤ እነዚህ ፡ የጋድ ፡ ልጆች ፡ የጭፍራ ፡ አለቆች ፡
ነበሩ ፤ ከእነርሱም ፡ ታናሹ ፡ ከመቶ ÷ ታላቁ ፡
፲፭፤ ከሺህ ፡ ይመዘዙ ፡ ነበር ። በመጀመሪያው ፡
ወር ፡ ዮርዳኖስ ፡ ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ ሞልቶ ፡
በነበረ ፡ ጊዜ ፡ የተሻገሩት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤
በሸለቆውም ፡ ውስጥ ፡ በምሥራቅና ፡ በምዕ
ራብ ፡ በኩል ፡ የተቀመጡትን ፡ ሁሉ ፡ አባረሩ ።
፲፮፤ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ ነበረበት ፡ ወደ ፡ አምባይቱ ፡
ከብንያምና ፡ ከይሁዳ ፡ ወገን ፡ ሰዎች ፡ መጡ ።
፲፯፤ ዳዊትም ፡ ሊገናኛቸው ፡ ወጥቶ ፦ ትረዱኝ ፡
ዘንድ ፡ በሰላም ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጥታችሁ ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ ልቤ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ይሆናል ፤
ለጠላቶቼ ፡ አሳልፋችሁ ፡ ልትሰጡኝ ፡ መጥታ
ችሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ÷ በእጄ ፡ ዓመፅ ፡ የለብ
ኝምና ፡ የአባቶቻችን ፡ አምላክ ፡ ይመልከተው ÷
፲፰፤ ይፍረደውም ፡ አላቸው ። መንፈስም ፡ በሠላ
ሳው ፡ አለቃ ፡ በዓማሣይ ፡ ላይ ፡ መጣ ÷ እር
ሱም ፦ ዳዊት ፡ ሆይ ÷ እኛ ፡ የአንተ ፡ ነን ፤
የእሴይ ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ እኛ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነን ፤
አምላክህ ፡ ይረዳሃልና ፡ ሰላም ፡ ሰላም ፡ ለአንተ ፡
ይሁን ÷ ለሚረዱህም ፡ ሰላም ፡ ይሁን ፡ አለ ።
ዳዊትም ፡ ተቀበላቸው ÷ የጭፍራም ፡ አለቆች ፡
አደረጋቸው ።
፲፱፤ ዳዊትም ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ ጋር ፡ ሳኦ
ልን ፡ ሊወጋ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ከምናሴ ፡ ወገን ፡
ሰዎች ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ከዱ ፤ የፍልስጥኤማው
ያን ፡ አለቆች ፡ ግን ፦ በራሳችን ፡ ላይ ፡ ጕዳት ፡
አድርጎ ፡ ወደ ፡ ጌታው ፡ ወደ ፡ ሳኦል ፡ ይመለ
ሳል ፡ ሲሉ ፡ ተማክረው ፡ ሰደደውታልና ፡ እነ
፳፤ ርሱ ፡ አልረዱአቸውም ። ወደ ፡ ጺቅላግም ፡
ሲሄድ ፡ ከምናሴ ፡ ወገን ፡ የምናሴ ፡ ሻለቆች ፡
የነበሩ ፡ ዓድና ÷ ዮዛባት ÷ ይዲኤል ÷ ሚካኤል ÷
ዮዛባት ÷ ኤሊሁ ÷ ጺልታይ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ከዱ ።
፳፩፤ ሁሉም ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላንና ፡ በሠራዊቱ ፡ ላይ ፡
አለቆች ፡ ነበሩና ፡ በአደጋ ፡ ጣዮቹ ፡ ላይ ፡ ዳዊ
፳፪፤ ትን ፡ አገዙት ። እንደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሠራ
ዊት ፡ ታላቅ ፡ ሠራዊት ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡ ዳዊ
ትን ፡ ለመርዳት ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ይመጡ ፡ ነበር ።
፳፫፤ እንደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ የሳኦልን ፡
መንግሥት ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ይመልሱ ፡ ዘንድ ፡
በኬብሮን ፡ ሳለ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ የመጡት ፡
የሠራዊቱ ፡ አለቆች ፡ ቍጥር ፡ ይህ ፡ ነው ።
፳፬፤ ጋሻና ፡ ጦር ፡ ተሸክመው ፡ ለሰልፍ ፡ የተዘጋጁ ፡
የይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ስድስት ፡ ሺህ ፡ ስምንት ፡
፳፭፤ መቶ ፡ ነበሩ ። ለሰልፍ ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡
ሰዎች ፡ የነበሩ ፡ የስምዖን ፡ ልጆች ፡ ሰባት ፡
፳፮፤ ሺህ ፡ አንድ ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። የሌዊ ፡ ልጆች ፡
፳፯፤ አራት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። የአሮ
ንም ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ ዮዳሄ ፡ ነበረ ÷ ከእርሱም ፡
፳፰፤ ጋር ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ፤ ከእ
ርሱም ፡ ጋር ፡ ጽኑዕ ፡ ኃያል ፡ ጕልማሳ ፡ ሳዶቅ ፡

ነበረ ÷ ከአባቱም ፡ ቤት ፡ ሀያ ፡ ሁለት ፡ አለቆች ፡
፳፱ ነበሩ ። የሳኦልም ፡ ወንድሞች ፡ ከሆኑ ፡ ከብን
ያም ፡ ልጆች ፡ የሚበልጠው ፡ ክፍል ፡ እስከ
ዚያ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ የሳኦልን ፡ ቤት ፡ ይከተል ፡
ነበርና ፡ ከእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ የመጡ ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡
፴ ነበሩ ። ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡ የሆኑ ፡ በአባቶቻ
ቸውም ፡ ቤት ፡ የታወቁ ፡ የኤፍሬም ፡ ልጆች ፡
፴፩ ሀያ ፡ ሺህ ፡ ስምንት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። በየስማቸ
ውም ፡ የተጻፉ ፡ ዳዊትን ፡ ያነግሡት ፡ ዘንድ ፡
የመጡ ፡ የምናሴ ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ አሥራ ፡
፴፪ ስምንት ፡ ሺህ ፡ ነበሩ ። እስራኤልም ፡ የሚገ
ባውን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ዘመኑን ፡ የሚያውቁ ፡
ጥበበኞች ፡ ሰዎች ፡ የይሳኮር ፡ ልጆች ፡ አለቆች ፡
ሁለት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ፤ ወንድሞቻቸውም ፡ ሁሉ ፡
፴፫ ይታዘዙአቸው ፡ ነበር ። በጭፍራውም ፡ ውስጥ ፡
የወጡ ፡ ለሰልፍም ፡ የተዘጋጁ ÷ የማያመነቱ ÷
መጣሪያም ፡ ሁሉ ፡ የያዙ ፡ የዛብሎን ፡ ሰዎች ፡
፴፬ አምሳ ፡ ሺህ ፡ ነበሩ ። የንፍታሌምም ፡ አለቆች ፡
አንድ ፡ ሺህ ፡ ነበሩ ÷ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ጋሻና ፡
ጦር ፡ የሚይዙ ፡ ሠላሳ ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡ ነበሩ ።
፴፭ ለሰልፍም ፡ የተዘጋጁ ፡ የዳን ፡ ሰዎች ፡ ሀያ ፡
፴፮ ስምንት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። በጭ
ፍራውም ፡ ውስጥ ፡ የሚወጡ ÷ ለሰልፍም ፡
የተዘጋጁ ፡ የአሴር ፡ ሰዎች ፡ አርባ ፡ ሺህ ፡ ነበሩ ።
፴፯ በዮርዳኖስም ፡ ማዶ ፡ ካሉ ፡ ከሮቤልና ፡ ከጋድ ፡
ሰዎች ፡ ከምናሴም ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ መሣሪ
ያን ፡ ሁሉ ፡ ይዘው ፡ የመጡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሺህ ፡
ነበሩ ።

፴፰ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ዳዊትን ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ ያነግሡት ፡ ዘንድ ፡ አርበኞችና ፡ ሰልፈ
ኞች ፡ እየሆኑ ፡ በፍጹም ፡ ልባቸው ፡ ወደ ፡
ኬብሮን ፡ መጡ ፤ ደግሞም ፡ ከእስራኤል ፡ የቀ
ሩት ፡ ሁሉ ፡ ዳዊትን ፡ ያነግሡት ፡ ዘንድ ፡ አንድ ፡
፴፱ ልብ ፡ ነበሩ ። ወንድሞቻቸውም ፡ አዘጋጅተ
ውላቸው ፡ ነበርና ፡ እየበሉና ፡ እየጠጡ ፡ በዚያ ፡
፵ ከዳዊት ፡ ጋር ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ተቀመጡ ። ደግ
ሞም ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ደስታ ፡ ሆኖአልና ፡
እስከ ፡ ይሳኮርና ፡ እስከ ፡ ዛብሎን ፡ እስከ ፡ ንፍ
ታሌምም ፡ ድረስ ፡ ለእርሱ ፡ አቅራቢያ ፡ የነበሩ ፡
በአህያና ፡ በግመል ፡ በበቅሎና ፡ በበሬ ፡ ላይ ፡
እንጀራና ፡ ዱቄት ፡ የበለስ ፡ ጥፍጥፍና ፡ የዘ
ቢብ ፡ ዘለላ ፡ የወይንም ፡ ጠጅ ፡ ዘይትም ፡ በሬ
ዎችንና ፡ በጎችንም ፡ በብዙ ፡ አድርገው ፡ ያመጡ ፡
ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ ዳዊትም ፡ ከሻለቆችና ፡ ከመቶ ፡ አለቆች ፡
፪ ከአለቆቹም ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ተማከረ ። ዳዊትም ፡
የእስራኤልን ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡— መልካም ፡
መስሎ ፡ የታያችሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ ከአምላክ
ችን ፡ ከእግዚአብሔርም ፡ ወጥቶ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷
በእስራኤል ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ለቀሩት ፡ ወንድሞ
ቻችን ፡ በከተሞቻቸውና ፡ በመሰምርያዎቻቸ
ውም ፡ ለሚቀመጡ ፡ ካህናትና ፡ ሌዋውያን ፡
ወደ ፡ እኛ ፡ ይሰበሰቡ ፡ ዘንድ ፡ እንላክ ፤ በሳ ፫
ኦልም ፡ ዘመን ፡ አልፈለግነውምና ፡ የአምላክ
ችንን ፡ ታቦት ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ እንመልስ ፡ አላ
ቸው ። ነገሩም ፡ በሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ዓይን ፡ ዘንድ ፡ ፬
ቅን ፡ ነበረና ፡ ጉባኤው ፡ ሁሉ ፡— እንዲሁ ፡
እናደርጋለን ፡ አሉ ። የእግዚአብሔርንም ፡ ፭
ታቦት ፡ ከቂርያትይዓሪም ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡
ዳዊት ፡ እስራኤልን ፡ ሁሉ ፡ ከግብጽ ፡ ወንዝ ፡
ከሺሖር ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሐማት ፡ መግቢያ ፡
ድረስ ፡ ሰበሰበ ። ዳዊትም ፡ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ፮
በኪሩቤል ፡ ላይ ፡ የተቀመጠውን ፡ ስሙም ፡
በእርሱ ፡ የተጠራውን ፡ የአምላክን ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ታቦት ፡ ከዚያ ፡ ያወጡ ፡ ዘንድ ፡ በይ
ሁዳ ፡ ወዳለችው ፡ ቂርያትይዓሪም ፡ ወደ ፡ ተበ
ለች ፡ ወደ ፡ በኣላ ፡ ሄዱ ። የእግዚአብሔርንም ፡ ፯
ታቦት ፡ በአዲስ ፡ ሰረገላ ፡ ላይ ፡ ጫኑት ÷ ከአሚ
ናዳብም ፡ ቤት ፡ አመጡት ፤ ዖዛና ፡ አሒዮም ፡
ሰረገላውን ፡ ይነዱ ፡ ነበር ። ዳዊትና ፡ እስራ ፰
ኤል ፡ ሁሉ ፡ በቅኔና ፡ በበገና ፡ በመሰንቆና ፡ በከ
በሮ ፡ በጸናጽልና ፡ በመለከት ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ በሙሉ ፡ ኃይላቸው ፡ ይጫወቱ ፡ ነበር ።

ወደ ፡ ኪዶንም ፡ አውድማ ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ ፱
በሬዎቹ ፡ ይፋንኑ ፡ ነበርና ፡ ታቦቱን ፡ ሊይዝ ፡
ዖዛ ፡ እጁን ፡ ዘረጋ ። የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ ፲
በዖዛ ፡ ላይ ፡ ነደደ ÷ እጁንም ፡ ወደ ፡ ታቦቱ ፡
ስለ ፡ ዘረጋ ፡ ቀሠፈው ፤ በዚያም ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ፊት ፡ ሞተ ። እግዚአብሔርም ፡ ዖዛን ፡ ፲፩
ስለ ፡ ቀሠፈው ፡ ዳዊት ፡ አዘነ ፤ እስከ ፡ ዛሬም ፡
ድረስ ፡ የዚያን ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ የዖዛ ፡ ስብራት ፡
ብሎ ፡ ጠራው ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ዳዊት ፡— የእ ፲፪
ግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዴት ፡
አመጣለሁ ? ብሎ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈራ ።

ዳዊትም ፡ ታቦቱን ፡ ወደ ፡ ጌት ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ፲፫
አቢዳራ ፡ ቤት ፡ አሳለፈው ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡
ወደ ፡ ዳዊት ፡ ከተማ ፡ አላመጣውም ። የእግዚ ፲፬
አብሔርም ፡ ታቦት ፡ በአቢዳራ ፡ ቤት ፡ ሰብ ፡
ዘንድ ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ ተቀመጠ ፤
እግዚአብሔርም ፡ የአቢዳራን ፡ ቤትና ፡ ያለ
ውን ፡ ሁሉ ፡ ባረከ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

የጢሮስም ፡ ንጉሥ ፡ ኪራም ፡ ቤት ፡ ይሠሩ ፩
ለት ፡ ዘንድ ፡ መልእክተኞችን ፡ የዝግባ ፡ እን
ጨትንም ፡ ጠራቢዎችንም ፡ አናጢዎችንም ፡
ወደ ፡ ዳዊት ፡ ላከ ። ስለ ፡ ሕዝቡም ፡ ስለ ፡ እስ ፪
ራኤል ፡ መንግሥቱ ፡ ከፍ ፡ ብሎአልና ፡ እግዚ
አብሔር ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ አድርጎ ፡
እንዳጸናው ፡ ዳዊት ፡ አወቀ ።

ዳዊትም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ሚስቶችን ፡ ፫
ጨምሮ ፡ ሌሎችን ፡ ወንዶችንና ፡ ሴቶችን ፡
ልጆች ፡ ወለደ ። በኢየሩሳሌምም ፡ የወለዳ ፬
ቸው ፡ የልጆቹ ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ሳሙስ ÷
ሰባብ ÷ ናታን ÷ ሰሎሞን ÷ ኢያቤሐር ÷ ኤሊ ፭
ሱዔ ÷ ኤሊፋላት ÷ ኖጋ ÷ ናፌቅ ÷ ያፍያ ÷ ፮

፯ ኤሊሳማ ÷ ኤሊዳሄ ÷ ኤሊፋላት ።
፰ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ዳዊት ፡ በእስራኤል ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ሆኖ ፡ እንደ ፡ ተቀባ ፡ ሰሙ ÷
ፍልስጥኤማውያንም ፡ ሁሉ ፡ ዳዊትን ፡ ሊፈ
ልጉ ፡ ወጡ ፤ ዳዊትም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ሊጋጠ
፱ ማቸው ፡ ወጣ ። ፍልስጥኤማውያንም ፡ መጥ
፲ ተው ፡ በራፋይም ፡ ሸለቆ ፡ አደጋ ፡ ጣሉ ። ዳዊ
ትም ፡— ወደ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ልውጣን ?
በእጄስ ፡ አሳልፈህ ፡ ትሰጣቸዋለህን ? ብሎ ፡
እግዚአብሔርን ፡ ጠየቀ ። እግዚአብሔርም ፡—
በእጅህ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣቸዋለሁና ፡ ውጣ ፡
፲፩ አለው ። ወደ ፡ በአልፐራሲምም ፡ ወጡ ÷
በዚያም ፡ ዳዊት ፡ መታቸው ። ዳዊትም ፡— ውኃ ፡
እንዲያፈርስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጠላቶቼን ፡ በእጄ ፡
አፈረሳቸው ፡ አለ ። ስለዚህም ፡ የዚያን ፡ ስፍራ ፡
፲፪ ስም ፡ በአልፐራሲም ፡ ብለው ፡ ጠሩት ። አማ
ልክቶቻቸውንም ፡ በዚያ ፡ ተዉ ፤ ዳዊትም ፡
አዘዘ ÷ በእሳትም ፡ አቃጠሉአቸው ።
፲፫ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ደግሞ ፡ በሸለቆው ፡
፲፬ አደጋ ፡ ጣሉ ። ዳዊትም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ ጠየቀ ፤ እግዚአብሔርም ፡— ከእነ
ርሱ ፡ ዞረህ ፡ በሾላው ፡ ዛፍ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡
ግጠማቸው ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ አትውጣ ።
፲፭ በሾላውም ፡ ዛፍ ፡ ራስ ፡ ውስጥ ፡ የሽውሽ
ውታ ፡ ድምፅ ፡ ስትሰማ ፡ የፍልስጥኤማውያ
ንን ፡ ጭፍራ ፡ ሊመታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በፊ
ትህ ፡ ይወጣልና ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡
፲፮ ውጣ ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ እግዚአብሔር ፡ እን
ዳዘዘው ፡ አደረገ ፤ ከገባዖንም ፡ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ጌዝር ፡ ድረስ ፡ የፍልስጥኤማውያንን ፡ ጭፍራ ፡
፲፯ መቱት ። የዳዊትም ፡ ዝና ፡ በየአገሩ ፡ ሁሉ ፡
ወጣ ፤ መፈራቱንም ፡ እግዚአብሔር ፡ በአሕ
ዛብ ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ አደረገው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ ዳዊትም ፡ በከተማው ፡ ላይ ፡ ለራሱ ፡ ቤቶ
ችን ፡ ሠራ ፤ ለእግዚአብሔርም ፡ ታቦት ፡
፪ ስፍራ ፡ አዘጋጀ ÷ ድንኳንም ፡ ተከለለት ። በዚ
ያን ፡ ጊዜም ፡ ዳዊት ፡— የእግዚአብሔርን ፡
ታቦት ፡ ይሸከሙ ፡ ዘንድ ÷ ለዘላለሙም ፡ ያገለ
ግሉት ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከመረጣቸው ፡
ከሌዋውያን ፡ በቀር ፡ ማንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ታቦት ፡ ይሸከም ፡ ዘንድ ፡ አይገባውም ፡ አለ ።
፫ ዳዊትም ፡ ወዳዘጋጀለት ፡ ስፍራ ፡ የእግዚአብ
ሔርን ፡ ታቦት ፡ ያመጣ ፡ ዘንድ ፡ እስራኤልን ፡
፬ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሰበሰበ ። ዳዊትም ፡
የአሮንን ፡ ልጆችና ፡ ሌዋውያንን ፡ ሰበሰበ ።
፭ ከቀዓት ፡ ልጆች ፤ አለቃው ፡ ኡርኤል ÷ ወንድ
፮ ሞቹም ፡ መቶ ፡ ሀያ ፤ ከሜራሪ ፡ ልጆች ፤ አለ
ቃው ፡ ዓሣያ ÷ ወንድሞቹም ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሀያ ፤
፯ ከጌድሶን ፡ ልጆች ፤ አለቃው ፡ ኢዮኤል ÷ ወን
፰ ድሞቹም ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፤ ከኤሊጻፋን ፡ ልጆች ፤
አለቃው ፡ ሸማያ ÷ ወንድሞቹም ፡ ሁለት ፡ መቶ ፤
፱ ከኬብሮን ፡ ልጆች ፤ አለቃው ፡ ኤሊኤል ÷ ወን
ድሞቹም ፡ ሰማንያ ፤ ከዑዝኤል ፡ ልጆች ፤ ፲
አለቃው ፡ አሚናዳብ ÷ ወንድሞቹም ፡ መቶ ፡
አሥራ ፡ ሁለት ። ዳዊትም ፡ ካህናቱን ፡ ሳዶቅ ፲፩
ንና ፡ አብያታርን ÷ ሌዋውያንንም ፡ ኡርኤልን ÷
ዓሣያን ÷ ኢዮኤልን ÷ ሸማያን ÷ ኤሊኤልን ÷
አሚናዳብንም ፡ ጠርቶ ፡— እናንተ ፡ የሌዋው ፲፪
ያን ፡ አባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ናችሁ ፤ ወዳ
ዘጋጀሁለት ፡ ስፍራ ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ታመጡ ፡ ዘንድ ፡
እናንተና ፡ ወንድሞቻችሁ ፡ ተቀደሱ ። ቀድ ፲፫
ሞም ፡ አልተሸከማችሁምና ÷ እንደ ፡ ሥርዓ
ቱም ፡ አልፈለግነውምና ፡ አምላካችን ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ በመካከላችን ፡ ስብራት ፡ አደረገ ፡
አላቸው ። የእስራኤልንም ፡ አምላክ ፡ የእግዚ ፲፬
አብሔርን ፡ ታቦት ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡ ካህናቱና ፡
ሌዋውያኑ ፡ ተቀደሱ ። ሙሴም ፡ እንዳዘዘው ፡ ፲፭
እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ የሌዋውያን ፡
ልጆች ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ በትከሻ
ቸው ፡ ላይ ፡ በመሎጊያዎቹ ፡ ተሸከሙ ።
ዳዊትም ፡ በዜማ ፡ ዕቃ ፡ በመሰንቆና ፡ በበ ፲፮
ገና ፡ በጸናጽልም ፡ እንዲያዜሙ ÷ ድምፃቸው
ንም ፡ በደስታ ፡ ከፍ ፡ እንዲያደርጉ ፡ መዘምራ
ኑን ፡ ወንድሞቻቸውን ፡ ይሾሙ ፡ ዘንድ ፡ ለሌ
ዋውያን ፡ አለቆች ፡ ተናገረ ። ሌዋውያኑም ፡ ፲፯
የኢዮኤልን ፡ ልጅ ፡ ኤማንን ÷ ከወንድሞቹም ፡
የበራክያን ፡ ልጅ ፡ አሳፍን ÷ ከወንድሞቻቸ
ውም ፡ ከሜራሪ ፡ ልጆች ፡ የቂሳን ፡ ልጅ ፡ ኤታ
ንን ÷ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ በሁለተኛው ፡ ተራ ፡ ፲፰
የሆኑትን ፡ ወንድሞቻቸውን ፡ ዘካርያስን ÷
ቤንን ÷ ያዝኤልን ÷ ሰሚራሞትን ÷ ይሒኤ
ልን ÷ ዑኒን ÷ ኤልያብን ÷ በናያስን ÷ መዕሤ
ያን ÷ መቲትያን ÷ ኤሊፍሌሁን ÷ ሚቅኔያን ÷
በረኞችንም ፡ ዖቤድኤዶምንና ፡ ይዒኤልን ፡
አቆሙ ። መዘምራንም ፡ ኤማንና ፡ አሳፍ ፡ ፲፱
ኤታንም ፡ በናስ ፡ ጸናጽል ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡
ያሰሙ ፡ ነበር ። ዘካርያስ ÷ ዓዝዔል ÷ ሰሚራ ፳
ሞት ÷ ይሒኤል ÷ ዑኒ ÷ ኤልያብ ÷ መዕሤያ ÷
በናያስ ፡ በመሰንቆ ፡ ምሥጢር ፡ ነገር ፡ ያዜሙ ፡
ነበር ። መቲትያ ÷ ኤልፍሌሁ ÷ ሚቅኔያ ÷ ፳፩
ዖቤድኤዶም ÷ ይዒኤል ÷ ዓዛዝያ ፡ ስምንት ፡
አውታር ፡ ባለው ፡ በገና ፡ ይዘምሩ ፡ ነበር ።
የሌዋውያኑም ፡ አለቃ ፡ ክናንያ ፡ በዜማ ፡ ላይ ፡ ፳፪
ተሾሞ ፡ ነበር ። ብልሃተኛ ፡ ነበረና ፡ ዜማ ፡ ያስ
ተምራቸው ፡ ነበር ። በራክያና ፡ ሕልቃናም ፡ ፳፫
ለታቦቱ ፡ በረኞች ፡ ነበሩ ። ካህናቱም ፡ ሰበኒያ ÷ ፳፬
ኢዮሣፍጥ ÷ ናትናኤል ÷ ዓማሣይ ÷ ዘካርያስ ÷
በናያስ ÷ አልዓዛር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡
ፊት ፡ መለከት ፡ ይነፉ ፡ ነበር ። ዖቤድኤዶ
ምና ፡ ይሒያም ፡ ለታቦቱ ፡ በረኞች ፡ ነበሩ ።
ዳዊትም ÷ የእስራኤልም ፡ሽማግሌዎች ÷ ፳፭
የሻለቆችም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የቃል ፡ ኪዳ
ኑን ፡ ታቦት ፡ ከአቢዳራ ፡ ቤት ፡ በደስታ ፡
ያመጡ ፡ ዘንድ ፡ ሄዱ ። የእግዚአብሔርንም ፡ ፳፮
ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ የተሸከሙትን ፡ ሌዋው

ያንን፡እግዚአብሔር፡በረዳቸው፡ጊዜ፡ሰባት፡
በሬዎችና ፡ ሰባት ፡ አውራ ፡ በጎች ፡ ሠዉ ።
፳፯፤ ዳዊትም ፥ ታቦቱንም ፡ የተሸከሙ ፡ ሌዋው
ያን ፡ ሁሉ ፥ መዘምራኑም ፥ የመዘምራኑም ፡
አለቃ ፡ ክናንያ ፡ የጥሩ ፡ በፍታ ፡ ቀሚስ ፡ ለብ
ሰው ፡ ነበር ፤ ዳዊትም ፡ የበፍታ ፡ ኤፉድ ፡ ነበ
፳፰፤ ረው ። እንዲሁ ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ሆ ፡
እያሉ ፥ ቀንደ ፡ መለከትና ፡ እምቢልታ ፡ እየ
ነፉ፥ጸናጽልና፡መሰንቆም፡በገናም፡እየመቱ፥
የእግዚአብሔርን ፡ የቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡
አመጡ ።
፳፱፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡
ወደ ፡ ዳዊት ፡ ከተማ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ የሳኦል ፡
ልጅ ፡ ሜልኮል ፡ በመስኮት ፡ ሆና ፡ ተመለከ
ተች ፤ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ሲዘፍንና ፡ ሲጫወት ፡
አይታ ፡ በልብዋ ፡ ናቀችው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ታቦት ፡ ይዘው ፡ ገቡ ፥
ዳዊትም ፡ በተከለለት ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ አኖ
ሩት ፤ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የደኅንነ
ቱን ፡ መሥዋዕትም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
፪፤ አቀረቡ ። ዳዊትም ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋ
ዕትና ፡ የደኅንነቱን ፡ መሥዋዕት ፡ ማቅረብ ፡
በፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ሕዝ
፫፤ ቡን ፡ ባረከ ። ለእስራኤልም ፡ ለወንዱም ፡ ለሴ
ቱም ፡ ለእያንዳንዱ ፡ አንዳንድ ፡ እንጀራ ፥ አን
ዳንድም ፡ ቊራጭ ፡ ሥጋ ፥ አንዳንድም ፡ የዘ
ቢብ ፡ ጥፍጥፍ ፡ አካፈለ ።
፬፤ በእግዚአብሔርም ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ ያገለግሉ ፡
ዘንድ ፥ የእስራኤልንም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ ይወድሱት ፡ ዘንድ ፥ ያመሰግኑትና ፡
ያከብሩትም ፡ ዘንድ ፡ ከሌዋውያን ፡ ወገን ፡
፭፤ አቆመ ። አለቃው ፡ አሳፍ ፡ ነበረ ፤ ከእርሱም ፡
በኋላ ፡ ዘካርያስ ፥ ይዒኤል ፥ ሰሚራሞት ፥
ይሒኤል ፥ መቲትያ ፥ ኤልያብ ፥ በናያስ ፥
ዖቤድኤዶም ፥ ይዒኤል ፡ በመሰንቆና ፡ በበገና ፡
፮፤ አሳፍም ፡ በጸናጽል ፡ ይዘምሩ ፡ ነበር ። ካህና
ቱም ፡ በናያስና ፡ የሕዚኤል ፡ በእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ ሁልጊዜ ፡ መለከት ፡
ይነፉ ፡ ነበር ።
፯፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ዳዊት ፡ በአሳፍና ፡ በወንድ
ሞቹ ፡ እጅ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዲያመሰግኑ ፡
አስቀድሞ ፡ ትእዛዝን ፡ ሰጠ ።

፰፤ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፥ ስሙን ፡ ጥሩ ፤
ለአሕዛብ ፡ ሥራውን ፡ አውሩ ።
፱፤ ተቀኙለት ፥ ዘምሩለት ፤
ተአምራቱንም ፡ ሁሉ ፡ ተናገሩ ።
፲፤ በቅዱስ ፡ ስሙ ፡ ተኳደዱ ፤
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈልግ ፡ ልብ ፡ ደስ ፡
ይበለው ።
፲፩፤ እግዚአብሔርን ፡ ፈልጉት ፥ ትጸናላች
ሁም ፤
ሁልጊዜ ፡ ፊቱን ፡ ፈልጉ ።
፲፪፡፲፫ በሪያዎቹ ፡ የእስራኤል ፡ ዘር ፥
ለእርሱም ፡ የተመረጣችሁ ፡ የያዕቆብ ፡
ልጆች ፡ ሆይ ፥
የሠራትን ፡ ድንቅ ፡ አስቡ ፥
ተአምራቱንም ፡ የአፉንም ፡ ፍርድ ።
፲፬፤ እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችን ፡ ነው ፤
ፍርዱ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ነው ።
ቃል ፡ ኪዳኑን ፡ ለዘላለም ፥
እስከ ፡ ሺህ ፡ ትውልድ ፡ ያዘዘውን ፡ ቃሉን ፡
አሰበ ፥
፲፮፤ ለአብርሃም ፡ ያደረገውን ፥
ለይስሐቅም ፡ የማለውን ፤
፲፯፤ ለያዕቆብ ፡ ሥርዓት ፡ እንዲሆን ፡
ለእስራኤልም ፡ የዘላለምን ፡ ኪዳን ፡ እንዲ
ሆን ፡ አጸና ፤
፲፰፤ እንዲህም ፡ አለ ፡— ለአንተ ፡ የከነዓንን ፡
ምድር ፡
የርስታችሁን ፡ ገመድ ፡ እሰጣለሁ ፤
፲፱፤ ይህም ፡ የሆነው ፡ እነርሱ ፡ በቊጥር ፡ ጥቂ
ቶች ፡ ሰዎች ፥
እጅግ ፡ ጥቂቶችና ፡ ስደተኞች ፡ ሲሆኑ ፡
ነው ።
፳፤ ከሕዝብ ፡ ወደ ፡ ሕዝብ ፥
ከመንግሥትም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ሕዝብ ፡ አለፉ ።
፳፩፤፳፪፤ የቀባኋቸውን ፡ አትዳስሱ ፥
በነቢያቴም ፡ ክፉ ፡ አታድርጉ ፡ ብሎ ፥
ሰው ፡ ግፍ ፡ ያደርግባቸው ፡ ዘንድ ፡ አል
ፈቀደም ፤
ስለ ፡ እነርሱም ፡ ነገሥታትን ፡ ገሠጸ ።
፳፫፤ ምድር ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፤
ዕለት ፡ ዕለት ፡ ማዳኑን ፡ አውሩ ።
፳፬፤ ክብሩን ፡ ለአሕዛብ ፥
ተአምራቱንም ፡ ለወገኖች ፡ ሁሉ ፡ ንገሩ ።
፳፭፤ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፥ ምስጋናውም ፡
ብዙ ፡ ነውና ፤
በአማልክትም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የተፈራ ፡ ነው ።
፳፮፤ የአሕዛብ ፡ አማልክት ፡ ሁሉ ፡ ጣዖታት ፡
ናቸው ፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ሰማያትን ፡ ሠራ ።
፳፯፤ ክብርና ፡ ግርማ ፡ በፊቱ ፥
ኃይልና ፡ ደስታ ፡ በስፍራው ፡ ውስጥ ፡
ናቸው ።
፳፰፤ የአሕዛብ ፡ ወገኖች ፡ ለእግዚአብሔር ፡
አምጡ ፥
ክብርንና ፡ ኃይልን ፡ ለእግዚአብሔር ፡
አምጡ ።
፳፱፤ ለስሙ ፡ የሚገባ ፡ ክብርን ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ አምጡ ፤
ቊርባንን ፡ ይዛችሁ ፡ በፊቱ ፡ ግቡ ፤
በቅድስናው ፡ ስፍራ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ስገዱ ።
፴፤ ምድር ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ትነዋወጥ ፤
ዓለሙም ፡ እንዳይናወጥ ፡ ጸንቶአል ።
፴፩፤ ሰማያት ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፥ ምድርም ፡

ሐሜትን ፡ ታድርግ ፤
በአሕዛብም ፡ መከከል ፡— እግዚአብሔር ፡
ነገሠ ፡ በሉ ።
፴፪፤ ባሕርና ፡ ሞላዋ ፡ ትናወጥ ፤
በረሀ ፡ በእርስዋም ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ ሐሜትን ፡
ያድርጉ ።
፴፫፤ በምድር ፡ ሊፈርድ ፡ ይመጣልና ÷
የዱር ፡ ዛፎች ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ፊት ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፴፬፤ ቸር ፡ ነውና ÷ ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡
ነውና ፡
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ።
፴፭፤ የመዳናችን ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ አድነን ፤
ቅዱስ ፡ ስምህን ፡ እናመሰግን ፡ ዘንድ ÷
በምስጋናህም ፡ እንመካ ፡ ዘንድ ÷
ከአሕዛብ ፡ ሰብስበህ ፡ ታደገን ፡ በሉ ።
፴፮፤ ከዘላለም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ÷
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡
ይበረክ ።
ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡ ይበሉ ፤ እግዚአብሔ
ርንም ፡ ያመስግኑ ።

፴፯፤ እንዲሁም ፡ በየቀኑ ፡ እንደሚገባቸው ፡ በታ
በቱ ፡ ፊት ፡ ዘወትር ፡ ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡ አሳፍ
ንና ፡ ወንድሞቹን ÷ ዖቤድኤዶምንም ÷ ስድሳ ፡
ስምንቱንም ፡ ወንድሞቻቸውን ፡ በዚያ ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ ፊት ፡ ተዋ
ቸው ።
፴፰፤ የኤዶታምም ፡ ልጅ ፡ ዖቤድኤዶምና ፡ ሖሳ ፡
፴፱፤ በረኞች ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ተዋቸው ። ካህኑን ፡
ሳዶቅንና ፡ ካህናቱን ፡ ወንድሞቹን ፡ በገባዖን ፡
በኮረብታው ፡ መስገጃ ፡ ባለው ፡ በእግዚአብ
፵፤ ሔር ፡ ማደሪያ ፡ ፊት ፡ አቆማቸው ÷ ለእስራኤ
ልም ፡ ባዘዘው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ እንደ ፡
ተጻፈ ፡ ሁሉ ፡ ለሚቃጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ በሚ
ሆነው ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥ
ዋዕት ፡ ሁልጊዜ ፡ ጥዋትና ፡ ማታ ፡ ለእግዚአብ
፵፩፤ ሔር ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ። ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡
ነውና ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ፡
ኤማንንና ፡ ኤዶታምን ÷ በስማቸውም ፡ የተጻ
ፉትን ፡ ተመርጠው ፡ የቀሩትን ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡
፵፪፤ አቆመ ። ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ካህናቱ ፡ ከፍ ፡
አድርገው ፡ ለማሰማት ፡ መለከትና ፡ ጸናጽል ፡
ለእግዚአብሔርም ፡ መዝሙራት ፡ የዜማ ፡ ዕቃ ፡
ይዘው ፡ ነበር ፤ የኤዶታምም ፡ ልጆች ፡ በረኞች ፡
፵፫፤ ነበሩ ። ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡
ሄደ ፤ ዳዊትም ፡ ቤቱን ፡ ይባርክ ፡ ዘንድ ፡ ተመ
ለሰ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ዳዊት ፡ በቤቱ ፡ በተቀመጠ ፡
ጊዜ ፡ ዳዊት ፡ ነቢዩን ፡ ናታንን ፡— እነሆ ÷ እኔ ፡
ከዝግባ ፡ በተሠራ ፡ ቤት ፡ ተቀምጫለሁ ፤ የእ
ግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ በመጋ
፪፤ ረጃዎች ፡ ውስጥ ፡ ተቀምጦአል ፡ አለው ። ናታ
ንም ፡ ዳዊትን ፡— እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡
ነውና ፡ በልብህ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ አድርግ ፡
፫፤ አለው ። በዚያም ፡ ሌሊት ፡ የእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ ወደ ፡ ናታን ፡ መጣ ፡ እንዲህም ፡ አለው ፡—
፬፡፭፤ ሂድ ÷ ለባሪያዬ ፡ ለዳዊት ፡ ንገረው ፡— እግዚአ
ብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እስራኤልን ፡ ካወ
ጣሁበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ከድ
ንኳን ፡ ወደ ፡ ድንኳን ÷ ከማደሪያም ፡ ወደ ፡ ማደ
ሪያ ፡ እሄድ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በቤት ፡ ውስጥ ፡
አልኖርሁምና ፡ የምኖርበትን ፡ ቤት ፡ አትሠራል
፮፤ ኝም ። ከእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ባለፍሁበት ፡
ስፍራ ፡ ሁሉ ፡— ስለ ፡ ምን ፡ ቤትን ፡ ከዝግባ ፡ እን
ጨት ፡ አልሠራችሁልኝም ? ብዬ ፡ ሕዝቤን ፡
ይጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ከእስራኤል ፡ ፈራጆች ፡ላዘዝ
፯፤ ሁት ፡ ለአንዱ ፡ በውኑ ፡ ተናግሬአለሁን ? አሁ
ንም ፡ ባሪያዬን ፡ ዳዊትን ፡ እንዲህ ፡ በለው ፡—
የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— አንተ ፡ መንጋውን ፡ ስትከተል ፡ በሕ
ዝቤ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡
፰፤ ከበግ ፡ ጥበቃ ፡ ወሰድሁህ ። በሄድህበትም ፡
ሁሉ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነበርሁ ÷ ጠላቶችህንም ፡
ሁሉ ፡ ከፊትህ ፡ አጠፋሁ ፤ በምድርም ፡ ላይ ፡
እንዳሉ ፡ እንደ ፡ ታላላቆች ፡ ስም ፡ ለአንተ ፡ ስም ፡
፱፡፲፤ አደርጋለሁ ። ለሕዝቤም ፡ ለእስራኤል ፡ ስፍራ ፡
አደርግለታለሁ ÷ እተክለውማለሁ ÷ በስፍራ
ውም ፡ ይቀመጣል ÷ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ አይና
ወጥም ፤ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ዘመንና ፡ በሕዝ
ቤም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ፈራጆች ፡ እንዳስነ
ሣሁበት ፡ ጊዜ ፡ ግፈኞች ፡ ተመልሰው ፡ አያስ
ጨንቁትም ፤ ጠላቶችህንም ፡ ሁሉ ፡ አዋርዳቸ
ዋለሁ ። እግዚአብሔር ፡ ደግሞ ፡ ቤት ፡ እንዲ
፲፩፤ ሠራልህ ፡ እነግርሃለሁ ። ወደ ፡ አባቶችህም ፡
ትሄድ ፡ ዘንድ ፡ ዕድሜህ ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡
ከልጆችህ ፡ የሚሆነውን ፡ ዘርህን ፡ ከአንተ ፡
በኋላ ፡ አስነሣለሁ ፤ መንግሥቱንም ፡ አጸናለሁ ።
፲፪፤ እርሱ ፡ ቤት ፡ ይሠራልኛል ፤ ዙፋኑንም ፡ ለዘላ
፲፫፤ ለም ፡ አጸናለሁ ። እኔም ፡ አባት ፡ እሆነዋለሁ ÷
እርሱም ፡ ልጅ ፡ ይሆነኛል ፤ ከአንተ ፡ አስቀ
ድሞ ፡ ከነበረው ፡ እንዳራቅሁ ÷ ምሕረቴን ፡ ከእ
፲፬፤ ርሱ ፡ አላርቅም ። በቤቴና ፡ በመንግሥቴም ፡
ለዘላለም ፡ አቆመዋለሁ ፤ ዙፋኑም ፡ ለዘላለም ፡
፲፭፤ ይጸናል ። እንደዚህ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እንደዚህም ፡
ራእይ ፡ ሁሉ ፡ ናታን ፡ ለዳዊት ፡ ነገረው ።

፲፮፤ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ገባ ÷ በእግዚአብሔርም ፡
ፊት ፡ ተቀምጦ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— አቤቱ ፡ አም
ላክ ፡ ሆይ ÷ እስከዚህ ፡ ያደረስኸኝ ፡ እኔ ፡ ማን ፡
፲፯፤ ነኝ ? ቤቴስ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አምላክ ፡ ሆይ ÷
ይህ ፡ በፊትህ ፡ ጥቂት ፡ ነበረ ፤ አቤቱ ፡ አምላክ ፡
ሆይ ÷ ስለ ፡ ባሪያህ ፡ ቤት ፡ ደግሞ ፡ ለሩቅ ፡
ዘመን ፡ ተናገርህ ፤ እንደ ፡ አንድ ፡ ባለ ፡ ማዕ
፲፰፤ ርግ ፡ ሰው ፡ ተመለከትኸኝ ። አንተ ፡ ባሪያህን ፡
ታውቀዋለህና ፡ ለባሪያህ ፡ ስለ ፡ ተደረገው ፡
ክብር ፡ ዳዊት ፡ ጨምሮ ፡ የሚለው ፡ ምንድር ፡
፲፱፤ ነው ? አቤቱ ÷ ይህን ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡

ታስታውቀው ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ባሪያህ ፡ እንደ ፡ ልብህም ፡ ይህን ፡ ተአምራት ፡ ሁሉ ፡ አድርገሃል ። ፳ አቤቱ ፥ እንደ ፡ አንተ ፡ ያለ ፡ የለም ፥ በጆሮአችንም ፡ እንደ ፡ ሰማን ፡ ሁሉ ፡ ከአንተ ፡ በቀር ፡ አምላክ ፡ የለም ። ፳፩ አንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከግብጽ ፡ ካወጣኸው ፡ ከሕዝብህ ፡ ፊት ፡ አሕዛብን ፡ በማሳደድ ፡ በታላቅና ፡ በሚያስፈራ ፡ ነገር ፡ ለአንተ ፡ ስም ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፥ ለአንተም ፡ ሕዝብ ፡ ትቤዥ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ሄድህለት ፡ እንደ ፡ አንተ ፡ ሕዝብ ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ ያለ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ሌላ ፡ ሕዝብ ፡ አለን ? ፳፪ ሕዝብህንም ፡ እስራኤልን ፡ ለዘላለም ፡ ሕዝብህ ፡ አደረግኸው ፤ አንተም ፥ አቤቱ ፥ አምላክ ፡ ሆንኸዋል ። ፳፫ አሁንም ፥ አቤቱ ፥ ስለ ፡ ባሪያህና ፡ ስለ ፡ ቤቱ ፡ የተናገርኸው ፡ ለዘላለም ፡ የጸና ፡ ይሁን ፤ እንደ ፡ ተናገርህም ፡ አድርግ ። ፳፬ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እርሱ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ነው ፥ በእውነት ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ ይባል ፡ ዘንድ ፡ ስምህ ፡ ለዘላለም ፡ ጽኑና ፡ ታላቅ ፡ ይሁን ፤ የባሪያህም ፡ የዳዊት ፡ ቤት ፡ በፊትህ ፡ ጸንቶአል ። ፳፭ አምላኬ ፡ ሆይ ፥ ቤት ፡ እንድትሠራለት ፡ ለባሪያህ ፡ ገልጠሃልና ፡ ስለዚህ ፡ ባሪያህ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ይጸልይ ፡ ዘንድ ፡ በልቡ ፡ ደፈረ ። ፳፮ አሁንም ፥ አቤቱ ፥ አንተ ፡ አምላክ ፡ ነህ ፥ ይህንም ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ለባሪያህ ፡ ተናግረሃል ። ፳፯ አሁንም ፡ በፊትህ ፡ ለዘላለም ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ የባሪያህን ፡ ቤት ፡ እንድትባርክ ፡ ፈቅደሃል ፤ አንተም ፥ አቤቱ ፥ ባርክኸዋል ፥ ለዘላለምም ፡ ቡሩክ ፡ ይሆናል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ዳዊት ፡ ፍልስጥኤማውያንን ፡ መታ ፥ አዋረዳቸውም ፥ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ እጅ ፡ ጌትንና ፡ መንደሮችዋን ፡ ወሰደ ። ፪ ሞዓብን ፡ መታ ፤ ሞዓባውያንም ፡ ለዳዊት ፡ ገባሮች ፡ ሆኑ ፥ ግብርም ፡ አመጡለት ።

፫ ዳዊትም ፡ በኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ የነበረውን ፡ ግዛት ፡ ለመያዝ ፡ በሄደ ፡ ጊዜ ፡ የሱባን ፡ ንጉሥ ፡ አድርአዛርን ፡ እስከ ፡ ሐማት ፡ ድረስ ፡ መታ ። ፬ ዳዊትም ፡ ከእርሱ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ ሰረገሎች ፥ ሰባት ፡ ሺህም ፡ ፈረሰኞች ፥ ሀያ ፡ ሺህም ፡ እግረኞች ፡ ወሰደ ፤ ዳዊትም ፡ ለመቶ ፡ ሰረገሎች ፡ የሚሆኑትን ፡ ብቻ ፡ አስቀርቶ ፡ የሰረገሎቹን ፡ ፈረሶች ፡ ቋንጃ ፡ ቆረጠ ።

፭ ከደማስቆም ፡ ሶርያውያን ፡ የሱባን ፡ ንጉሥ ፡ አድርአዛርን ፡ ሊረዱ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ዳዊት ፡ ከሶርያውያን ፡ ሀያ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ሰዎችን ፡ ገደለ ። ፮ ዳዊትም ፡ በደማስቆ ፡ ሶርያ ፡ ጭፍሮች ፡ አኖረ ፤ ሶርያውያንም ፡ ለዳዊት ፡ ገባሮች ፡ ሆኑ ፥ ግብርም ፡ አመጡለት ። እግዚአብሔርም ፡ ዳዊት ፡ በሄደበት ፡ ሁሉ ፡ ድል ፡ ይሰጠው ፡ ነበር ። ፯ ዳዊትም ፡ ለአድርአዛር ፡ ባሪያዎች ፡ የነበሩትን ፡ የወርቅ ፡ ጋሻዎች ፡ ወሰደ ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ይዞአቸው ፡ መጣ ። ፰ ከአድርአዛርም ፡ ከተሞች ፡ ከጢብሐትና ፡ ከኩን ፡ ዳዊት ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ናስ ፡ ወሰደ ፤ ከዚህም ፡ ሰሎሞን ፡ የናሱን ፡ ኵሬና ፡ ዓምዶች ፡ የናሱንም ፡ ዕቃ ፡ ሠራ ።

፱ የሐማትም ፡ ንጉሥ ፡ ቶዑ ፡ ዳዊት ፡ የሱባን ፡ ንጉሥ ፡ የአድርአዛርን ፡ ጭፍራ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ መታ ፡ ሰማ ። ፲ ቶዑም ፡ ከአድርአዛር ፡ ጋር ፡ ሁልጊዜ ፡ ይዋጋ ፡ ነበርና ፡ ዳዊት ፡ አድርአዛርን ፡ ወግቶ ፡ ስለ ፡ መታው ፡ ደኅንነቱን ፡ ይጠይቅ ፡ ዘንድ ፡ ይመርቀውም ፡ ዘንድ ፡ ልጁን ፡ አዶራምን ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ላከው ፤ እርሱም ፡ የወርቅና ፡ የብር ፡ የናስም ፡ ዕቃ ፡ ይዞ ፡ መጣ ። ፲፩ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ከኤዶምና ፡ ከሞዓብ ፡ ከአሞንም ፡ ልጆች ፡ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ ከአማሌቅም ፡ ከማረከው ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ ጋር ፡ እነዚህን ፡ ደግሞ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቀደሰ ።

፲፪ ደግሞ ፡ የጽሩያ ፡ ልጅ ፡ አቢሳ ፡ ከኤዶማውያን ፡ በጨው ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ አሥራ ፡ ስምንት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ገደለ ። ፲፫ በኤዶምያስም ፡ ጭፍሮች ፡ አኖረ ፥ ኤዶማውያንም ፡ ሁሉ ፡ ለዳዊት ፡ ገባሮች ፡ ሆኑ ። እግዚአብሔርም ፡ ዳዊት ፡ በሄደበት ፡ ሁሉ ፡ ድል ፡ ይሰጠው ፡ ነበር ።

፲፬ ዳዊትም ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነገሠ ፤ ለሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ፍርድንና ፡ ጽድቅን ፡ አደረገላቸው ። ፲፭ የጽሩያ ፡ ልጅ ፡ ኢዮአብም ፡ የሠራዊት ፡ አለቃ ፡ ነበረ ፤ የአሒሉድም ፡ ልጅ ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ ታሪክ ፡ ጸሐፊ ፡ ነበረ ። ፲፮ የአኪጦብም ፡ ልጅ ፡ ሳዶቅ ፥ የአቤሜሌክም ፡ ልጅ ፡ አብያታር ፡ ካህናት ፡ ነበሩ ፤ ሱሳ ፡ ጸሐፊ ፡ ነበረ ። ፲፯ የዮዳሄ ፡ ልጅ ፡ በናያስ ፡ በከሊታውያንና ፡ በፈሊታውያን ፡ ላይ ፡ ነበረ ፤ የዳዊትም ፡ ልጆች ፡ በንጉሡ ፡ አጠገብ ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የአሞን ፡ ልጆች ፡ ንጉሥ ፡ ናዖስ ፡ ሞተ ፥ ልጁም ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ። ፪ ዳዊትም ፡— አባቱ ፡ ስላደረገልኝ ፡ ወረታ ፡ እኔ ፡ ለናዖስ ፡ ልጅ ፡ ለሐኖን ፡ ቸርነት ፡ አደርጋለሁ ፡ አለ ። ዳዊትም ፡ አባቱ ፡ ስለ ፡ ሞተ ፡ ሊያጽናናው ፡ መልእክተኞችን ፡ ላከ ፤ የዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡ ሊያጽናኑት ፡ ወደ ፡ ሐኖን ፡ ወደ ፡ አሞን ፡ ልጆች ፡ ምድር ፡ መጡ ። ፫ የአሞን ፡ ልጆች ፡ አለቆች ፡ ግን ፡ ሐኖንን ፡— ዳዊት ፡ አባትህን ፡ አክብሮ ፡ የሚያጽናኑህን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ የላከ ፡ ይመስልሃልን ? ባሪያዎቹስ ፡ አገሪቱን ፡ ለመመርመር ፥ ለማጥፋት ፥ ለመሰለልም ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ የመጡ ፡ አይደሉምን ? አሉት ። ፬ ሐኖንም ፡ የዳዊትን ፡ ባሪያዎች ፡ ወስዶ ፡ አስላጫቸው ፥ ልብሳቸውንም ፡ እስከ ፡ ወገባቸው ፡ ድረስ ፡ ከሁለት ፡ ቀድዶ ፡ ሰደዳቸው ። ፭ ወሬኞችም ፡ ሄደው ፡ በሰዎቹ ፡ ላይ ፡ የተደረገውን ፡ ለዳዊት ፡ አስታወቁት ። ሰዎ

ቹም ፡ በብዙ ፡ አፍረዋልና ፡ ተቀበዮች ፡ ላከ ፤ ንጉሡም ፦ ጢማችሁ ፡ እስኪያድግ ፡ ድረስ ፡ በኢያሪኮ ፡ ተቀመጡ ÷ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ተመለሱ ፡ አለ ።

፮ የአሞንም ፡ ልጆች ፡ በዳዊት ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተጠሉ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ሐኖንና ፡ የአሞን ፡ ልጆች ፡ ከመስጴጦምያ ÷ ከአራምመዓካ ÷ ከሱባ ፡ ሰረገሎችንና ፡ ፈረሰኞችን ፡ ይቀጥሩ ፡ ዘንድ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ መክሊት ፡ ብር ፡ ላኩ ።
፯ ሠላሳ ፡ ሁለትም ፡ ሺህ ፡ ሰረገሎች ፡ የመዓካንም ፡ ንጉሥ ፡ ሕዝቡንም ፡ ቀጠሩ ፤ መጥተውም ፡ በሜድባ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ሰፈሩ ። የአሞንም ፡ ልጆች ፡ ከየከተሞቻቸው ፡ ተሰብስበው ፡ ወደ ፡
፰ ሰልፍ ፡ መጡ ። ዳዊትም ፡ ይህን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ኢዮአብንና ፡ የኃያላኑን ፡ ሠራዊት ፡
፱ ሁሉ ፡ ላከ ። የአሞንም ፡ ልጆች ፡ ወጥተው ፡ በከተማይቱ ፡ በር ፡ አጠገብ ፡ ተሰለፉ ፤ የመጡትም ፡ ነገሥታት ፡ ለብቻቸው ፡ በሜዳው ፡ ላይ ፡ በሩ ።

፲ ኢዮአብም ፡ በፊትና ፡ በኋላ ፡ ሰልፍ ፡ እንደ ፡ ከበበው ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ከእስራኤል ፡ ምርጥ ፡ ምርጦችን ፡ ሁሉ ፡ ለይቶ ፡ በሶርያውያን ፡ ላይ ፡
፲፩ አሰለፋቸው ። የቀረውንም ፡ ሕዝብ ፡ ለወንድሙ ፡ ለአቢሳ ፡ ሰጠው ÷ በአሞንም ፡ ልጆች ፡
፲፪ ላይ ፡ ተሰለፉ ። እርሱም ፦ ሶርያውያን ፡ ቢበረቱብኝ ፡ እርዳኝ ፤ የአሞንም ፡ ልጆች ፡ ቢበረ
፲፫ ቱብህ ፡ እረዳሃለሁ ። አይዞህ ÷ ስለ ፡ ሕዝባችንና ፡ ስለ ፡ አምላካችንም ፡ ከተሞች ፡ እንበርታ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ደስ ፡ ያሰኘውን ፡ ያድርግ ፡
፲፬ አለ ። ኢዮአብና ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበረው ፡ ሕዝብ ፡ ለሰልፍ ፡ ወደ ፡ ሶርያውያን ፡ ፊት ፡
፲፭ ቀረቡ ÷ እነርሱም ፡ ከፊቱ ፡ ሸሹ ። የአሞንም ፡ ልጆች ፡ ሶርያውያን ፡ እንደ ፡ ሸሹ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ እነርሱ ፡ ደግሞ ፡ ከወንድሙ ፡ ከአቢሳ ፡ ፊት ፡ ሸሹ ÷ ወደ ፡ ከተማይቱም ፡ ገቡ ። ኢዮአብም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጣ ።

፲፮ ሶርያውያንም ፡ በእስራኤል ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ተሸነፉ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ መልእክተኞች ፡ ልከው ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ የነበሩትን ፡ ሶርያውያን ፡ አስመጡ ፤ የአድርአዛርም ፡ ሠራዊት ፡ አለቃ ፡
፲፯ ሾፋክ ፡ በፊታቸው ፡ ነበረ ። ዳዊትም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ እስራኤልን ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰበ ÷ ዮርዳኖስንም ፡ ተሻግሮ ፡ መጣባቸው ÷ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ተዋጋ ፤ ዳዊትም ፡ በሶርያውያን ፡ ላይ ፡ በተሰለፈ ፡ ጊዜ ፡ እነርሱ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተዋጉ ።
፲፰ ሶርያውያንም ፡ ከእስራኤል ፡ ፊት ፡ ሸሹ ፤ ዳዊትም ፡ ከሶርያውያን ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡ ሰረገለኞች ÷ አርባ ፡ ሺህም ፡ እግረኞች ፡ ገደለ ÷ የሠራዊቱ
፲፱ ንም ፡ አለቃ ፡ ሾፋክን ፡ ገደለ ። የአድርአዛርም ፡ ባሪያዎች ፡ በእስራኤል ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ተሸነፉ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ከዳዊት ፡ ጋር ፡ ታረቁ ÷ ገበሩለትም ፤ ሶርያውያንም ፡ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ የአሞንን ፡ ልጆች ፡ ይረዱ ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ አሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በዓመት ፡ መለወጫ ፡ ነገሥታት ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ በሚወጡበት ፡ ጊዜ ፡ ኢዮአብ ፡ ሠራዊቱን ፡ አወጣ ÷ የአሞንንም ፡ ልጆች ፡ አገር ፡ አጠፋ ፤ መጥቶም ፡ ረባትን ፡ ከበበ ። ዳዊትም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ቈይቶ ፡ ነበር ።
፪ ኢዮአብም ፡ ረባትን ፡ መትቶ ፡ አፈረሳት ። ዳዊትም ፡ የንጉሣቸውን ፡ ዘውድ ፡ ከራሱ ፡ ላይ ፡ ወሰደ ÷ ክብደቱም ፡ አንድ ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፡ ያህል ፡ ነበረ ÷ ክቡርም ፡ ዕንቍ ፡ ነበረበት ÷ በዳዊትም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ አስቀመጡት ፤ ከከተ
፫ ማይቱም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ምርኮ ፡ አወጣ ። በውስጥዋም ፡ የነበረውን ፡ ሕዝብ ፡ አውጥቶ ፡ በመጋዝና ፡ በብረት ፡ መቈፈሪያ ፡ በመጥረቢያም ፡ እንዲሠሩ ፡ አደረጋቸው ። እንዲሁም ፡ ዳዊት ፡ በአሞን ፡ ልጆች ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ አደረገ ። ዳዊትም ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ።

፬ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በጌዝር ፡ ላይ ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ ጋር ፡ ሰልፍ ፡ ሆነ ፤ ኩሳታዊውም ፡ ሴቦካይ ፡ ከራፋይም ፡ ወገን ፡ የነበረውን ፡ ሲፋይን ፡ ገደለ ። ደግሞም ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡
፭ ጋር ፡ ሰልፍ ፡ ነበረ ፤ የያዒርም ፡ ልጅ ፡ ኤልያናን ፡ የጦሩ ፡ የቦ ፡ እንደ ፡ ሸማኔ ፡ መጠቅለያ ፡ የነበረውን ፡ የጌት ፡ ሰው ፡ የጎልያድን ፡ ወንድም ፡
፮ ለሕሚን ፡ ገደለ ። ደግሞ ፡ በጌት ፡ ላይ ፡ ሰልፍ ፡ ነበረ ፤ ከዚያም ፡ በእጁና ፡ በእግሩ ፡ ስድስት ፡ ስድስት ፡ ሁላሁሉ ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ጣቶች ፡ ያሉት ፡ አንድ ፡ ረጅም ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ እርሱም ፡
፯ ደግሞ ፡ ከራፋይም ፡ የተወለደ ፡ ነበረ ። እስራኤልንም ፡ በተገዳደረ ፡ ጊዜ ፡ የዳዊት ፡ ወንድም ፡
፰ የሳምዓ ፡ ልጅ ፡ ዮናታን ፡ ገደለው ። እነዚያም ፡ በጌት ፡ ውስጥ ፡ ከራፋይም ፡ የተወለዱ ፡ ነበሩ ፤ በዳዊትም ፡ እጅ ፡ በባሪያዎቹም ፡ እጅ ፡ ወደቁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ ሰይጣንም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ተነሣ ÷ እስራኤልንም ፡ ይቈጥር ፡ ዘንድ ፡ ዳዊትን ፡ አንቀ
፪ ሳቀሰው ። ዳዊትም ፡ ኢዮአብንና ፡ የሕዝቡን ፡ አለቆች ፦ ሂዱ ÷ ከቤርሳቤህ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዳን ፡ ድረስ ፡ እስራኤልን ፡ ቍጠሩ ÷ ድምራቸውንም ፡ አውቅ ፡ ዘንድ ፡ አስታውቁኝ ፡ አላ
፫ ቸው ። ኢዮአብም ፦ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ በአሁኑ ፡ ላይ ፡ መቶ ፡ እጥፍ ፡ ይጨምር ፤ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ ሁሉ ፡ የጌታዬ ፡ ባሪያዎች ፡ አይደሉምን ? ይህን ፡ ነገር ፡ ጌታዬ ፡ ለምን ፡ ይሻል ? በእስራኤል ፡ ላይ ፡ በደል ፡
፬ ስለ ፡ ምን ፡ ያመጣል ? አለ ። ነገር ፡ ግን ፡ የንጉሡ ፡ ቃል ፡ በኢዮአብ ፡ ላይ ፡ አሸነፈ ፤ ኢዮአብም ፡ ወጥቶ ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ተዘ
፭ ዋወረ ÷ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ መጣ ። ኢዮአብም ፡ የቈጠራቸውን ፡ የሕዝቡን ፡ ድምር ፡ ለዳ

ዊት ፡ ሰጠ ፤ ከእስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ ሚሊ
ዮን ፡ ከመቶ ፡ ሺህ ፡ ሰይፍ ፡ የሚመዝዙ ፡ ሰዎ
ችን ፡ አገኘ ፤ ከይሁዳም ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡
፮ ሺህ ፡ ሰይፍ ፡ የሚመዝዙ ፡ ሰዎችን ፡ አገኘ ። የን
ጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ ግን ፡ በኢዮአብ ፡ ዘንድ ፡ የተ
ጠላ ፡ ነበረና ፡ ሌዊና ፡ ብንያም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡
አልተቈጠሩም ።

፯ ከዚህም ፡ ነገር ፡ የተነሣ ፡ እግዚአብሔር ፡
፰ ተቈጣ ÷ እስራኤልንም ፡ ቀሠፈ ። ዳዊትም ፡
እግዚአብሔርን ፡— ይህን ፡ በማድረግ ፡ እጅግ ፡
በድያለሁ ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ታላቅ ፡ ስንፍና ፡ አድ
ርጌአለሁና ፡ የባሪያህን ፡ ኃጢአት ፡ ታስወግድ ፡
፱ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለው ። እግዚአብሔ
፲ ርም ፡ ለዳዊት ፡ ባለ ፡ ራእይ ፡ ለጋድ ፡— ሂድ ÷
ለዳዊት ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ሦስቱን ፡ ነገሮች ፡ በፊትህ ፡ አኖራለሁ ፤ አደር
ግብህ ፡ ዘንድ ፡ ከእነርሱ ፡ አንዱን ፡ ምረጥ ፡
፲፩ ብለህ ፡ ንገረው ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ። ጋድም ፡
ወደ ፡ ዳዊት ፡ መጥቶ ፡— እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— የምትወድደውን ፡ ምረጥ ፤
፲፪ የሦስት ፡ ዓመት ፡ ራብ ÷ ወይም ፡ ሦስት ፡ ወር ፡
የጠላቶችህ ፡ ሰይፍ ፡ እንዲያገኝህ ፡ ከጠላቶ
ችህ ፡ መሰደድን ÷ ወይም ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ የእግ
ዚአብሔር ፡ ሰይፍ ፡ ቸነፈርም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡
መሆንን ÷ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ በእ
ስራኤል ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ማጥፋትን ፡ ምረጥ ፤
አሁንም ፡ ለላከኝ ፡ ምን ፡ እንድመልስ ፡ ተመ
፲፫ ልከት ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ ጋድን ፡— እጅግ ፡
ተጨንቄአለሁ ፤ ምሕረቱ ፡ ብዙ ፡ ነውና ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ልውደቅ ፤ በሰው ፡ እጅ ፡
ግን ፡ አልውደቅ ፡ አለው ።

፲፬ እግዚአብሔርም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ቸነፈ
ርን ፡ ሰደደ ፤ ከእስራኤልም ፡ ሰባ ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡
፲፭ ወደቁ ። እግዚአብሔርም ፡ ያጠፋት ፡ ዘንድ ፡
ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መልአክን ፡ ሰደደ ፤ ሊያጠ
ፋትም ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ አይቶ ፡
ስለ ፡ ክፉው ፡ ነገር ፡ ተጸጸተ ÷ የሚያጠፋው
ንም ፡ መልአክ ፡— በቃህ ፤ አሁን ፡ እጅህን ፡
መልስ ፡ አለው ። የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡
በኢያቡሳዊው ፡ በኦርና ፡ አውድማ ፡ አጠገብ ፡
፲፮ ቆሞ ፡ ነበር ። ዳዊትም ፡ ዓይኖቹን ፡ አነሣ ፤
የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ በምድርና ፡ በሰ
ማይ ፡ መካከል ፡ ቆሞ ÷ የተመዘዘም ፡ ሰይፍ ፡
በእጁ ፡ ሆኖ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተዘርግቶ ፡
አየ ። ዳዊትም ፡ ሽማግሌዎችም ፡ ማቅ ፡ ለብ
፲፯ ሰው ፡ በግምባራቸው ፡ ተደፉ ። ዳዊትም ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡— ሕዝቡ ፡ ይቈጠር ፡ ዘንድ ፡ ያዘ
ዝሁ ፡ እኔ ፡ አይደለሁምን ? የበደልሁና ፡ ክፉ ፡
የሠራሁ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ እነዚህ ፡ በጎች ፡ ግን ፡
ምን ፡ አድርገዋል ? አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ÷
እጅህ ፡ በእኔና ፡ በአባቴ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ ትሁን ÷
ነገር ፡ ግን ፡ ይቀሠፍ ፡ ዘንድ ፡ በሕዝብህ ፡ ላይ ፡
አትሁን ፡ አለው ።

፲፰ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ዳዊት ፡ ወጥቶ ፡
በኢያቡሳዊው ፡ በኦርና ፡ አውድማ ፡ ላይ ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ለዳ
፲፱ ዊት ፡ እንዲነግረው ፡ ጋድን ፡ አዘዘው ። ዳዊ
ትም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ እንደ ፡ ተናገ
፳ ረው ፡ እንደ ፡ ጋድ ፡ ነገር ፡ ወጣ ። ኦርናም ፡
ዘወር ፡ ብሎ ፡ መልአኩን ፡ አየ ÷ ከእርሱም ፡ ጋር ፡
የነበሩ ፡ አራቱ ፡ ልጆቹ ፡ ተሸሸጉ ፤ ኦርናም ፡
፳፩ ስንዴ ፡ ያበራይ ፡ ነበር ። ዳዊትም ፡ ወደ ፡ ኦርና ፡
በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ኦርና ፡ ተመልክቶ ፡ ዳዊትን ፡
አየ ፤ ከአውድማውም ፡ ወጥቶ ፡ ዳዊትን ፡ እጅ ፡
፳፪ ሊነሣ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ተደፋ ። ዳዊትም ፡ ኦር
ናን ፡— በላዩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡
እሠራ ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡ የአውድማ ፡ ስፍራ ፡
ስጠኝ ፤ በሙሉ ፡ ዋጋ ፡ ስጠኝ ፤ መቅሠፍቱም ፡
፳፫ ከሕዝቡ ፡ ይከለከላል ፡ አለው ። ኦርናም ፡ ዳዊ
ትን ፡— ለአንተ ፡ ውሰደው ÷ ጌታዬ ፡ ንጉሡም ፡
ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡ ያድርግ ፤ እነሆ ÷ ለሚቃ
ጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ በሬዎቹን ÷ ለእንጨትም ፡
የአውድማውን ፡ ዕቃ ÷ ለእህልም ፡ ቍርባን ፡
ስንዴውን ፡ እሰጥሃለሁ ፤ ሁሉን ፡ እሰጣለሁ ፡
፳፬ አለው ። ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ኦርናን ፡— አይደ
ለም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ለአንተ ፡ ያለውን ፡ ለእግ
ዚአብሔር ፡ አምጥቼ ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋ
ዕት ፡ በከንቱ ፡ አላቀርብምና ፡ በሙሉ ፡ ዋጋ ፡
፳፭ እገዛዋለሁ ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ ስለ ፡ ስፍራው ፡
ስድስት ፡ መቶ ፡ ሰቅል ፡ ወርቅ ፡ በሚዛን ፡ ለኦ
፳፮ ርና ፡ ሰጠው ። ዳዊትም ፡ በዚያ ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ መሠዊያ ፡ ሠራ ÷ የሚቃጠለውን ፡ መሥ
ዋዕትና ፡ የደኅንነቱን ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረበ ÷
እግዚአብሔርንም ፡ ጠራ ፤ ከሰማይም ፡ ለሚቃ
ጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ በሚሆነው ፡ መሠዊያ ፡
፳፯ ላይ ፡ በእሳት ፡ መለሰለት ። እግዚአብሔርም ፡
መልአኩን ፡ አዘዘው ÷ ሰይፉንም ፡ በአፎቱ ፡
ከተተው ።

፳፰ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ በኢያቡሳ
ዊው ፡ በኦርና ፡ አውድማ ፡ እንደ ፡ መለሰለት ፡
ዳዊት ፡ በየ ፡ ጊዜ ÷ በዚያ ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዋ ።
፳፱ ሙሴም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የሠራት ፡ የእግዚአ
ብሔር ፡ ማደሪያና ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡
የሚሆነው ፡ መሠዊያ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በገባዖን ፡
፴ ባለው ፡ በኮረብታው ፡ መስገጃ ፡ ነበሩ ። ዳዊት ፡
ግን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መልአክ ፡ ሰይፍ ፡ ስለ ፡
ፈራ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመጠየቅ ፡ ወደዚያ ፡
ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ አልቻለም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ ዳዊትም ፡— ይህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
ነው ÷ ይህም ፡ ለእስራኤል ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥ
ዋዕት ፡ የሚሆነው ፡ መሠዊያ ፡ ነው ፡ አለ ።
፪ ዳዊትም ፡ በእስራኤል ፡ ምድር ፡ የነበሩትን ፡
መጻተኞች ፡ ይሰበስቡ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ የእግዚ
አብሔርንም ፡ ቤት ፡ ለመሥራት ፡ የሚወቀሩትን ፡
ድንጋዮች ፡ ይወቅሩ ፡ ዘንድ ፡ ጠራቢዎችን ፡
፫ አኖረ ። ዳዊትም ፡ ለበሮቹ ፡ ሳንቃ ፡ ለሚሆኑ ፡

ለምስማርና ፡ ለመጠረቂያ ፡ ብዙ ፡ ብረት ፥ ከብ
ዛቱም ፡ የተነሣ ፡ የማይመዘን ፡ ናስ ፡ አዘጋጀ ።
፬ ሲዶናውያንና ፡ የጢሮስ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ የዝ
ግባ ፡ እንጨት ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ያመጡ ፡ ነበርና ፡
ቍጥር ፡ የሌላቸውን ፡ የዝግባ ፡ እንጨቶች ፡ አዘ
፭ ጋጀ ። ዳዊትም ፡— ልጄ ፡ ሰሎሞን ፡ ታናሽና ፡
ለጋ ፡ ብላቴና ፡ ነው ፥ ለእግዚአብሔርም ፡ የሚ
ሠራው ፡ ቤት ፡ እጅግ ፡ ማለፊያና ፡ በአገሩ ፡
ሁሉ ፡ ስሙና ፡ ክብሩ ፡ እንዲጠራ ፡ ይሆን ፡
ዘንድ ፡ ይገባል ፤ ስለዚህ ፡ አዘጋጅለታለሁ ፡
አለ ። ዳዊትም ፡ ሳይሞት ፡ አስቀድሞ ፡ ብዙ ፡
አዘጋጀ ።

፮ ልጁንም ፡ ሰሎሞንን ፡ ጠርቶ ፡ ለእስራኤል ፡
አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ቤት ፡ ይሠራ ፡
፯ ዘንድ ፡ አዘዘው ። ዳዊትም ፡ ሰሎሞንን ፡ እንዲህ ፡
አለ ፡— ልጄ ፡ ሆይ ፥ እኔ ፡ ለአምላኬ ፡ ለእግዚ
አብሔር ፡ ቤት ፡ እሠራ ፡ ዘንድ ፡ በልቤ ፡ አስቤ ፡
፰ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እን
ዲህ ፡ ሲል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጣ ፡— እጅግ ፡ ደም ፡
አፍስሰሃል ፥ ታላቅም ፡ ሰልፍ ፡ አድርገሃል ፤
በፊቴ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ደም ፡ አፍስሰሃ
፱ ልና ፡ ለስሜ ፡ ቤት ፡ አትሠራም ። እነሆ ፥ የዕረ
ፍት ፡ ሰው ፡ የሚሆን ፡ ልጅ ፡ ይወለድልሃል ፤
በዙሪያው ፡ ካሉ ፡ ከጠላቶቹ ፡ ሁሉ ፡ አሳርፈዋ
ለሁ ፤ ስሙ ፡ ሰሎሞን ፡ ይባላልና ፥ በዘመኑም ፡
ሰላምንና ፡ ጸጥታን ፡ ለእስራኤል ፡ እሰጣለሁ ።
፲ እርሱ ፡ ለስሜ ፡ ቤት ፡ ይሠራል ፥ ልጅም ፡
ይሆነኛል ፥ እኔም ፡ አባት ፡ እሆነዋለሁ ፤ የመን
ግሥቱንም ፡ ዙፋን ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ለዘላ
፲፩ ለም ፡ አጸናለሁ ። አሁንም ፥ ልጄ ፡ ሆይ ፥ እግ
ዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፤ ስለ ፡ አን
ተም ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ ያከናውንልህ ፥ የአ
ምላክህንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ሥራ ።
፲፪ ብቻ ፡ የአምላክህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡
ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጥበብንና ፡
ማስተዋልን ፡ ይስጥህ ፥ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡
፲፫ ያሠልጥንህ ። እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡
ሙሴን ፡ ያዘዘውን ፡ ሥርዓትና ፡ ፍርድ ፡ ታደ
ርግ ፡ ዘንድ ፡ ብትጠነቀቅ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ይከ
ናወንልሃል ፤ አይዞህ ፥ በርታ ፤ አትፍራ ፥ አት
፲፬ ደንግጥም ። አሁንም ፥ እነሆ ፥ በድህነቴ ፡ ለእግ
ዚአብሔር ፡ ቤት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ መክሊት ፡ ወር
ቅና ፡ አንድ ፡ ሚሊዮን ፡ መክሊት ፡ ብር ፥ ሚዛ
ንም ፡ የሌላቸው ፡ ብዙ ፡ ናስና ፡ ብረት ፡ አዘጋ
ጀሁ ፤ ደግሞም ፡ እንጨትና ፡ ድንጋዮች ፡ አዘ
ጋጀሁ ፥ አንተም ፡ ከዚያ ፡ በላይ ፡ ጨምር ።
፲፭ በአንተም ፡ ዘንድ ፡ ብዙ ፡ ሠራተኞች ፥ ድንጋ
ይና ፡ እንጨት ፡ ወቃሪዎችና ፡ ጠራቢዎች ፥
ሥራውንም ፡ ሁሉ ፡ ለማድረግ ፡ ጠቢባን ፡ ሰዎች ፡
፲፮ ሁሉ ፡ አሉ ። የሚሠሩበት ፡ ወርቅና ፡ ብር ፡
ናስና ፡ ብረት ፡ ቍጥር ፡ የለውም ፤ ተነሥተህ ፡
ሥራ ፥ እግዚአብሔርም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይሁን ።
፲፯ ዳዊትም ፡ ደግሞ ፡ ልጁን ፡ ሰሎሞንን ፡ ያግዙ ፡
ዘንድ ፡ የእስራኤልን ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡
ሲል ፡ አዘዛቸው ፡— አምላካችሁ ፡ እግዚአብ ፲፰
ሔር ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ አይደለምን ? በምድ
ርም ፡ የሚቀመጡትን ፡ በእጄ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥ
ቶአልና ፥ ምድርም ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በሕ
ዝቡ ፡ ፊት ፡ ተገዝታለችና ፡ በዙሪያችሁ ፡ ሁሉ ፡
ዕረፍትን ፡ ሰጥቶአችኋል ። አሁንም ፡ አምላካ ፲፱
ችሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትፈልጉ ፡ ዘንድ ፡
ልባችሁንና ፡ ነፍሳችሁን ፡ ስጡ ፤ ለእግዚአብ
ሔርም ፡ ስም ፡ ወደሚሠራው ፡ ቤት ፡ የእግዚ
አብሔርን ፡ የቃል ፡ ኪዳኑን ፡ ታቦትና ፡ የእግዚ
አብሔርን ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳት ፡ ታመጡ ፡ ዘንድ ፡
ተነሥታችሁ ፡ የአምላክን ፡ የእግዚአብሔርን ፡
መቅደስ ፡ ሥሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ ዳዊትም ፡ በሸመገለ ፡ ጊዜ ፥ ዕድሜንም ፡ በጠ
ገበ ፡ ጊዜ ፡ ልጁን ፡ ሰሎሞንን ፡ በእስራኤል ፡
፪ ላይ ፡ አነገሠው ። የእስራኤልንም ፡ አለቆች ፡
ሁሉ ፥ ካህናቱንም ፥ ሌዋውያኑንም ፡ ሰበሰበ ።
፫ ሌዋውያንም ፡ ከሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ዕድሜ ፡ ጀምሮ ፡
ወደ ፡ ላይ ፡ ተቈጠሩ ፤ ቍጥራቸው ፡ በእያንዳ
ንዱ ፡ ነፍስ ፡ ወከፍ ፡ ሠላሳ ፡ ስምንት ፡ ሺህ ፡
፬ ነበረ ። ከእነዚህም ፡ ውስጥ ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ቤት ፡ ሥራ ፡ የሚያሠሩት ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡
ነበሩ ፤ ስድስቱ ፡ ሺህም ፡ አለቆችና ፡ ፈራጆች ፡
፭ ነበሩ ። አራቱ ፡ ሺህም ፡ በረኞች ፡ ነበሩ ፤
አራቱ ፡ ሺህም ፡ ለምስጋና ፡ በተሠሩት ፡ በዜማ ፡
ዕቃዎች ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግኑ ፡ ነበር ።
፮ ዳዊትም ፡ እንደ ፡ ሌዊ ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ጌድ
ሶንና ፡ እንደ ፡ ቀዓት ፡ እንደ ፡ ሜራሪም ፡ በየሰ
፯ ሞናቸው ፡ ከፈላቸው ። ከጌድሶናውያን ፡ ለአ
፰ ዳንና ፡ ሰሚኢ ፡ ነበሩ ። የለአዳን ፡ ልጆች ፡
አለቃው ፡ ይሒኤል ፥ ዜቶም ፥ ኢዮኤል ፡ ሦስት ፡
፱ ነበሩ ። የሰሚኢ ፡ ልጆች ፡ ሰሎሚት ፥ ሐዝ
ኤል ፥ ሐራን ፡ ሦስት ፡ ነበሩ ። እነዚህ ፡ የለአ
፲ ዳን ፡ አባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ። የሰ
ሚኢ ፡ ልጆች ፡ ኢኢት ፥ ዚዛ ፥ የዑስ ፥ በሪዓ ፡
ነበሩ ። እነዚህ ፡ አራቱ ፡ የሰሚኢ ፡ ልጆች ፡
፲፩ ነበሩ ። አለቃው ፡ ኢኢት ፡ ነበረ ፤ ሁለተኛው ፡
ዚዛ ፡ ነበረ ፤ የዑስና ፡ በሪዓ ፡ ግን ፡ ብዙ ፡
ልጆች ፡ አልነበሩአቸውም ፤ ስለዚህ ፡ እንደ ፡
አንድ ፡ አባት ፡ ቤት ፡ ሆነው ፡ ተቈጠሩ ።

፲፪ የቀዓት ፡ ልጆች ፡ እንበረም ፥ ይስዓር ፥ ኬብ
፲፫ ሮን ፥ ዑዝኤል ፡ አራት ፡ ነበሩ ። የእንበረም ፡
ልጆች ፡ አሮንና ፡ ሙሴ ፡ ነበሩ ፤ አሮንም ፡
ከሁሉ ፡ በላይ ፡ የተቀደሰ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ተለየ ፥
እርሱና ፡ ልጆቹ ፥ ለዘላለም ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ያጥንና ፡ ያገለግል ፡ ዘንድ ፥ በስሙም ፡
፲፬ ለዘላለም ፡ ይባርክ ፡ ዘንድ ። የእግዚአብሔ
ርም ፡ ሰው ፡ የሙሴ ፡ ልጆች ፡ በሌዊ ፡ ነገድ ፡
፲፭ ተቈጠሩ ። የሙሴ ፡ ልጆች ፡ ጌርሳምና ፡ አልዓ
፲፮ ዛር ፡ ነበሩ ። የጌርሳም ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡ ሱባ
፲፯ ኤል ፡ ነበረ ። የአልዓዛርም ፡ ልጆች ፡ አለቃ ፡
ረዓብያ ፡ ነበረ ፤ አልዓዛርም ፡ ሌሎች ፡ ልጆች ፡

አልነበሩትም ፤ የረዓብያ ፡ ልጆች ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡
፲፰ ነበሩ ። የይስዓር ፡ ልጆች ፡ አለቃው ፡ ሰሎሚት ፡
፲፱ ነበረ ። የኬብሮን ፡ ልጆች ፡ አለቃው ፡ ይሪያ ፥
ሁለተኛው ፡ አማርያ ፥ ሦስተኛው ፡ የሕዚኤል ፥
፳ አራተኛው ፡ ይቅምዓም ፡ ነበሩ ። የዑዝኤል ፡
ልጆች ፡ አለቃው ፡ ሚካ ፥ ሁለተኛው ፡ ይሺያ ፡
ነበሩ ።

፳፩ የሜራሪ ፡ ልጆች ፡ ሞሖሊና ፡ ሙሲ ፡ ነበሩ ።
የሞሖሊ ፡ ልጆች ፡ አልዓዛርና ፡ ቂስ ፡ ነበሩ ።
፳፪ አልዓዛርም ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ ወን
ዶች ፡ ልጆች ፡ ሳይወልድ ፡ ሞተ ፤ ወንድሞቻ
፳፫ ቸውም ፡ የቂስ ፡ ልጆች ፡ አገቡአቸው ። የሙሲ ፡
ልጆች ፡ ሞሖሊ ፥ ዔደር ፥ ኢያሪሙት ፡ ሦስት ፡
ነበሩ ።

፳፬ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ አገልግሎት ፡ በሠሩ ፡
ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ዕድሜ ፡ ጀምሮ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ በነ
በሩ ፡ በእያንዳንዳቸው ፡ በስማቸው ፡ በተቆጠ
ሩት ፡ ላይ ፡ የአባቶች ፡ ቤት ፡ አለቆች ፡ የሆኑት ፡
በየአባቶቻቸው ፡ ቤት ፡ የሌዊ ፡ ልጆች ፡ እነ
፳፭ ዚሁ ፡ ነበሩ ። ዳዊትም ፡— የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ፡ ዕረፍት ፡ ሰጥ
ቶአል ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ለዘላለም ፡ ይቀመ
፳፮ ጣል ። ሌዋውያንም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
ማደሪያውንና ፡ የማገልገያውን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡
፳፯ አይሸከሙም ፡ አለ ። በመጨረሻውም ፡ በዳ
ዊት ፡ ትእዛዝ ፡ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ዕድሜ ፡ ጀምሮ ፡
ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያሉት ፡ የሌዊ ፡ ልጆች ፡ ተቈ
፳፰ ጠሩ ። ሥራቸውም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡
በየአደባባዩና ፡ በየጓዳው ፡ ውስጥ ፡ ለማገል
ገል ፥ ቅዱሱንም ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ለማንጻት ፥
የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ አገልግሎት ፡ ለመ
ሥራት ፡ ከአሮን ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ በታች ፡ ነበረ ።
፳፱ ደግሞም ፡ ገጹ ፡ ኅብስት ፥ ስስ ፡ ቂጣም ፡ ቢሆን ፥
በምጣድም ፡ ቢጋገር ፥ ቢለወስም ፥ ለእህል ፡
ቍርባን ፡ በሆነው ፡ በመልክሙ ፡ ዱቄት ፡ በመ
ስፈሪያና ፡ በልክ ፡ ሁሉ ፡ ያገለግሉ ፡ ነበር ።
፴ ሥራቸውም ፡ በየጥዋቱና ፡ በየማታው ፡
ቆመው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለማመስገንና ፡ ለማ
፴፩ ክበር ፥ በየሰንበታቱም ፡ በየመባቻዎቹም ፡ በየ
በዓላቱም ፡ እንደ ፡ ሥርዓቱ ፡ ቍጥር ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ፊት ፡ ዘወትር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃ
፴፪ ጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ሁሉ ፡ ለማቅረብ ፥ ለእ
ግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ አገልግሎት ፡ የመገናኛ
ውን ፡ ድንኳን ፡ ሥርዓት ፡ የመቅደሱንም ፡
ሥርዓት ፡ የወንድሞቻቸውንም ፡ የአሮንን ፡
ልጆች ፡ ሥርዓት ፡ ለመጠበቅ ፡ ነበረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ሰሞን ፡ ይህ ፡ ነው ። የአ
ሮን ፡ ልጆች ፡ ናዳብ ፥ አብዩድ ፥ አልዓዛር ፥ ኢታ
፪ ምር ፡ ነበሩ ። ናዳብና ፡ አብዩድ ፡ ግን ፡ ልጆች ፡
ሳይወልዱ ፡ ከአባታቸው ፡ በፊት ፡ ሞቱ ፤ አል
፫ ዓዛርና ፡ ኢታምርም ፡ ከህናት ፡ ሆኑ ። ዳዊትም ፡
ከአልዓዛር ፡ ልጆች ፡ ከሳዶቅ ፡ ጋር ፥ ከኢታም
ርም ፡ ልጆች ፡ ከአቢሜሌክ ፡ ጋር ፡ ሆኖ ፡ እንደ ፡
አገልግሎታቸው ፡ ሥርዓት ፡ ከፍሎ ፡ መደበ
ቸው ። ፬ የአልዓዛርም ፡ ልጆች ፡ አለቆች ፡ ከኢ
ታምር ፡ ልጆች ፡ አለቆች ፡ በልጠው ፡ ተገኙ ፤
እንዲህም ፡ ተመደቡ ፤ ከአልዓዛር ፡ ልጆች ፡
እንደ ፡ አባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ አሥራ ፡ ስድ
ስት ፥ ከኢታምርም ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ አባቶቻ
ቸው ፡ ቤቶች ፡ ስምንት ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ። ፭ ከአ
ልዓዛርና ፡ ከኢታምርም ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡
የመቅደሱና ፡ የእግዚአብሔር ፡ አለቆች ፡ ነበ
ሩና ፡ እነዚህና ፡ እነዚያ ፡ እንዲሁ ፡ በዕጣ ፡ ተመ
ደቡ ። ፮ ከሌዋውያንም ፡ ወገን ፡ የነበረው ፡ የና
ትናኤል ፡ ልጅ ፡ ጸሐፊው ፡ ሸማያ ፡ በንጉሡና ፡
በአለቆቹ ፡ ፊት ፥ በካህኑ ፡ በሳዶቅና ፡ በአብያታ
ርም ፡ ልጅ ፡ በአቢሜሌክ ፡ ፊት ፥ በካህናቱና ፡
በሌዋውያኑ ፡ አባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ፊት ፡
ጻፋቸው ፤ አንዱንም ፡ የአባት ፡ ቤት ፡ ለአልዓ
ዛር ፥ አንዱንም ፡ ለኢታምር ፡ ጻፈ ።

፯ መጀመሪያውም ፡ ዕጣ ፡ ለዮአሪብ ፡ ወጣ ፥
፰ ሁለተኛው ፡ ለዮዳኤ ፥ ሦስተኛው ፡ ለካሪም ፥
፱ አራተኛው ፡ ለሥዖሪም ፥ አምስተኛው ፡ ለመ
፲ ልክያ ፥ ስድስተኛው ፡ ለሚያሚን ፥ ሰባተኛው ፡
፲፩ ለአቆስ ፥ ስምንተኛው ፡ ለአብያ ፥ ዘጠኛው ፡
፲፪ ለኢያሱ ፥ አሥረኛው ፡ ለሴኬንያ ፥ አሥራ ፡
አንደኛው ፡ ለኤልያሴብ ፥ አሥራ ፡ ሁለተኛው ፡
፲፫ ለያቂም ፥ አሥራ ፡ ሦስተኛው ፡ ለኦፓ ፥ አሥራ ፡
፲፬ አራተኛው ፡ ለየሼብአብ ፥ አሥራ ፡ አምስተ
ኛው ፡ ለቢልጋ ፥ አሥራ ፡ ስድስተኛው ፡ ለኢ
፲፭ ሜር ፥ አሥራ ፡ ሰባተኛው ፡ ለኤዚር ፥ አሥራ ፡
፲፮ ስምንተኛው ፡ ለሃፊጼጽ ፥ አሥራ ፡ ዘጠኛው ፡
፲፯ ለፈታያ ፥ ሀያኛው ፡ ለኤዜቄል ፥ ሀያ ፡ አንደ
ኛው ፡ ለያኪን ፥ ሀያ ፡ ሁለተኛው ፡ ለጋሙል ፥
፲፰ ሀያ ፡ ሦስተኛው ፡ ለድላያ ፥ ሀያ ፡ አራተኛው ፡
፲፱ ለመዓዝያ ። የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዳዘዘ ፥ አባታቸው ፡ አሮን ፡ እንደ ፡
ሰጣቸው ፡ ሥርዓት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ የሚገቡበት ፡ የአገልግሎታቸው ፡ ሥር
ዓት ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

፳ ከቀሩትም ፡ የሌዊ ፡ ልጆች ፤ ከእንበረም ፡
ልጆች ፡ ሱባኤል ፤ ከሱባኤል ፡ ልጆች ፡ ዩሕድያ ፤
፳፩ ፳፪ ከረዓብያ ፡ ልጆች ፡ አለቃው ፡ ይሺያ ፤ ከይስ
ዓራውያን ፡ ሰሎሚት ፤ ከሰሎሚት ፡ ልጆች ፡
፳፫ ያሐት ፤ ከኬብሮንም ፡ ልጆች ፡ አለቃው ፡ ይሪያ ፥
ሁለተኛው ፡ አማርያ ፥ ሦስተኛው ፡ የሕዚኤል ፥
፳፬ አራተኛው ፡ ይቀምዓም ፤ የዑዝኤል ፡ ልጅ ፡
፳፭ ሚካ ፤ የሚካ ፡ ልጅ ፡ ሻሚር ፤ የሚካ ፡ ወንድም ፡
፳፮ ይሺያ ፤ ከይሺያ ፡ ልጆች ፡ ዘካርያስ ፤ የሜራሪ ፡
ልጆች ፡ ሞሖሊ ፥ ሙሲ ፤ የያዝያ ፡ ልጅ ፡ በኖ ፤
፳፯ የሜራሪ ፡ ልጆች ፤ ከያዝያ ፡ በኖ ፥ ሾሃም ፥
፳፰ ዘኩር ፥ ዔብሪ ፤ ከሞሖሊ ፡ አልዓዛር ፥ እርሱም ፡
፳፱ ልጆች ፡ አልነበሩትም ፤ ከቂስ ፤ የቂስ ፡ ልጅ ፡
፴ ይረሕምኤል ፤ የሙሲም ፡ ልጆች ፤ ሞሖሊ ፥
ዔዳር ፥ ኢያሪሙት ። እነዚህ ፡ እንደ ፡ አባቶቻ
፴፩ ቸው ፡ ቤቶች ፡ የሌዋውያን ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ። እነ

ዚህም ፡ ደግሞ ፡ በንጉሡ ፡ በዳዊትና ፡ በሳዶቅ ፡
በአቢሜሌክም ፡ በሌዋውያንና ፡ በካህናት ፡ አባ
ቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ፊት ÷ ታላቁም ፡ እንደ ፡
ታናሹ ÷ እንደ ፡ ወንድሞቻቸው ፡ እንደ ፡ አሮን ፡
ልጆች ፡ ዕጣ ፡ ተጣጣሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

፩ ዳዊትና ፡ የሠራዊቱ ፡ አለቆችም ፡ ከአሳፍና ፡
ከኤማን ፡ ከኤዶታም ፡ ልጆች ፡ በመሰንቆና ፡
በበገና ፡ በጸናጽልም ፡ ትንቢት ፡ የሚናገሩትን ፡
ሰዎች ፡ ለማገልገል ፡ ለዩ ፤ በአገልግሎታቸ
ውም ፡ ሥራ ፡ የሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ቍጥር ፡ ይህ ፡
፪ ነበረ ። ከአሳፍ ፡ ልጆች ፤ ዘኩር ÷ ዮሴፍ ÷ ነታ
ንያ ÷ አሸርኤላ ፤ እነዚህ ፡ የአሳፍ ፡ ልጆች ፡ በን
ጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ ትንቢት ፡ ከተናገረው ፡ ከአ
፫ ሳፍ ፡ እጅ ፡ በታች ፡ ነበሩ ። ከኤዶታም ፡ የኤ
ዶታም ፡ ልጆች ፤ ጎዶልያስ ÷ ጽሪ ÷ የሻያ ÷
ሰሜኢ ÷ ሐሸብያ ÷ መቲትያ ÷ እነዚህ ፡ ስድ
ስቱ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምስጋናና ፡ ክብር ፡ በመ
ሰንቆ ፡ ትንቢት ፡ ከተናገረው ፡ ከአባታቸው ፡
፬ ከኤዶታም ፡ እጅ ፡ በታች ፡ ነበሩ ። ከኤማን ፡
የኤማን ፡ ልጆች ፤ ቡቅያ ÷ መታንያ ÷ ዓዛርዔል ÷
ሱባኤል ÷ ኢያሪሙት ÷ ሐናንያ ÷ ሐናኒ ÷ ኤል
ያታ ÷ ጊዶልቲ ÷ ሮማንቲዔዘር ÷ ዮሽብቃሻ ÷
፭ መሎቲ ÷ ሆቲር ÷ መሐዝዮት ፤ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡
ቀንደ ፡ መለከቱን ፡ ከፍ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ የንጉሡ ፡ ባለ ፡ ራእይ ፡
የሆነው ፡ የኤማን ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ። እግዚአብ
ሔርም ፡ ለኤማን ፡ አሥራ ፡ አራት ፡ ወንዶች ፡
ልጆችንና ፡ ሦስት ፡ ሴቶች ፡ ልጆችን ፡ ሰጠው ።
፮ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በጸና
ጽልና ፡ በበገና ፡ በመሰንቆም ፡ ይዘምሩ ፡ ዘንድ ÷
በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡
ከአባታቸው ፡ እጅ ፡ በታች ፡ ነበሩ ፤ አሳፍም ፡
ኤዶታምም ፡ ኤማንም ፡ ከንጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡
፯ በታች ፡ ነበሩ ። የብልሃተኞቹም ፡ ቍጥር ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ ለማመስገን ፡ ከሚያውቁ ፡ ከወ
ንድሞቻቸው ፡ ጋር ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡
፰ ስምንት ፡ ነበረ ። ሁሉም ፡ ተከክለው ÷ ታናሹ ፡
እንደ ፡ ታላቁ ÷ አስተማሪውም ፡ እንደ ፡ ተማ
ሪው ÷ ለሰሞናቸው ፡ ዕጣ ፡ ተጣጣሉ ።
፱ የፊተኛው ፡ ዕጣ ፡ ከአሳፍ ፡ ወገን ፡ ለነበረው ፡
ለዮሴፍ ፡ ወጣ ፤ ሁለተኛው ፡ ለጎዶልያስ ፡ ወጣ ፤
እርሱ ፡ ወንድሞቹም ፡ ልጆቹም ፡ አሥራ ፡
፲ ሁለት ፡ ነበሩ ፤ ሦስተኛው ፡ ለዘኩር ፡ ለልጆ
፲፩ ቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤ አራ
ተኛው ፡ ለይጽሪ ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡
፲፪ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤ አምስተኛው ፡ ለነታንያ ፡
ለልጆቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤
፲፫ ስድስተኛው ፡ ለቡቅያ ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድሞ
፲፬ ቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤ ሰባተኛው ፡ ለይሸር
ኤል ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለአሥራ ፡
፲፭ ሁለቱ ፤ ስምንተኛው ፡ ለየሻያ ፡ ለልጆቹም ፡
፲፮ ለወንድሞቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤ ዘጠኛኛው ፡
ለመታንያ ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለአ
፲፯ ሥራ ፡ ሁለቱ ፤ አሥረኛው ፡ ለሰሜኢ ፡ ለልጆ
ቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤
፲፰ አሥራ ፡ አንደኛው ፡ ለዓዛርኤል ፡ ለልጆቹም ፡
፲፱ ለወንድሞቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤ አሥራ ፡
ሁለተኛው ፡ ለሐሸብያ ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድሞ
፳ ቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤ አሥራ ፡ ሦስተኛው ፡
ለሱባኤል ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለአ
፳፩ ሥራ ፡ ሁለቱ ፤ አሥራ ፡ አራተኛው ፡ ለመቲ
ትያ ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለአሥራ ፡
፳፪ ሁለቱ ፤ አሥራ ፡ አምስተኛው ፡ ለኢያሪሙት ፡
ለልጆቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤
፳፫ አሥራ ፡ ስድስተኛው ፡ ለሐናንያ ፡ ለልጆቹም ፡
፳፬ ለወንድሞቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤ አሥራ ፡
ሰባተኛው ፡ ለዮሽብቃሻ ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድ
፳፭ ሞቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤ አሥራ ፡ ስምንተ
ኛው ፡ ለሐናኒ ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለአ
፳፮ ሥራ ፡ ሁለቱ ፤ አሥራ ፡ ዘጠኝኛው ፡ ለመሎቲ ፡
ለልጆቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤
፳፯ ሀያኛው ፡ ለኤልያታ ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድሞ
፳፰ ቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤ ሀያ ፡ አንደኛው ፡ ለሆ
ቲር ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለአሥራ ፡
፳፱ ሁለቱ ፤ ሀያ ፡ ሁለተኛው ፡ ለጊዶልቲ ፡ ለልጆ
፴ ቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤ ሀያ ፡
ሦስተኛው ፡ ለመሐዝዮት ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድ
፴፩ ሞቹም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤ ሀያ ፡ አራተኛው ፡
ለሮማንቲዔዘር ፡ ለልጆቹም ፡ ለወንድሞቹም ፡
ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ወጣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩ በረኞችም ፡ እንደዚህ ፡ ተመደቡ ፤ ከቆሬያ
ውያን ፡ ከአሳፍ ፡ ልጆች ፡ የቆሬ ፡ ልጅ ፡ ሜሱ
፪ ላም ። ሜሱላም ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ፤ በኵሩ ፡
ዘካርያስ ÷ ሁለተኛው ፡ ይዲኤል ÷ ሦስተኛው ፡
፫ ዮዛባት ÷ አራተኛው ፡ የትኒኤል ÷ አምስተ
ኛው ፡ ኤላም ÷ ስድስተኛው ፡ ይሆሐናን ÷
፬ ሰባተኛው ፡ ኤሊሆዔናይ ። እግዚአብሔርም ፡
ባርከታልና ፡ ዖቤድኤዶም ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ፤
በኵሩ ፡ ሸማያ ÷ ሁለተኛው ፡ ዮዛባት ÷ ሦስተ
ኛው ፡ ኢዮአስ ÷ አራተኛው ፡ ሣካር ÷ አምስ
፭ ተኛው ፡ ናትናኤል ÷ ስድስተኛው ፡ ዓሚኤል ÷
ሰባተኛው ፡ ይሳኮር ÷ ስምንተኛው ፡ ፒላቲ ።
፮ ለልጁም ፡ ለሸማያ ፡ ደግሞ ፡ ልጆች ፡ ተወለዱ
ለት ፤ ጽኑዓንም ፡ ኃያላን ፡ ነበሩና ፡ በአባታ
፯ ቸው ፡ ቤት ፡ ሠለጠኑ ። የሸማያ ፡ ልጆች ፤
ዖትኒ ÷ ራፋኤል ÷ ዖቤድ ÷ ወንድሞቹም ፡
ኃያላን ፡ የነበሩ ፡ ኤልዛባድ ÷ ኤሊሁ ÷ ሰማክያ ።
፰ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የዖቤድኤዶም ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ፤
እነርሱም ፡ ልጆቻቸውም ፡ ወንድሞቻቸውም ፡
ለማገልገል ፡ ኃያላን ፡ የነበሩ ፡ የዖቤድኤዶም ፡
፱ ልጆች ፡ ስድሳ ፡ ሁለት ፡ ነበሩ ። ለሜሱላም ፡
ኃያላን ፡ የነበሩ ፡ አሥራ ፡ ስምንት ፡ ልጆችና ፡
፲ ወንድሞች ፡ ነበሩት ። ከሜራሪም ፡ ልጆች ፡
ለነበረው ፡ ለሖሳ ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ፤ አለቃውም ፡

ሽምሪ ፡ ነበረ ፤ በኵር ፡ አልነበረም ፥ አባቱ ፡
፲፩ ግን ፡ አለቃ ፡ አደረገው ፤ ሁለተኛውም ፡ ኬል
ቅያስ ፥ ሦስተኛው ፡ ጥበልያ ፥ አራተኛው ፡
ዘካርያስ ፡ ነበረ ፤ የሖሳ ፡ ልጆችና ፡ ወንድሞች ፡
ሁሉ ፡ አሥራ ፡ ሦስት ፡ ነበሩ ።

፲፪ እንደ ፡ ወንድሞቻቸው ፡ ሆነው ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ቤት ፡ ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡ የበረኞች ፡
፲፫ የአለቆች ፡ ሰሞነኞች ፡ እነዚህ ፡ ነበሩ ። በበ
ሩም ፡ ሁሉ ፡ ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡ በየአባቶቻቸው ፡
ቤቶች ፡ ታናሹና ፡ ታላቁ ፡ ተካክለው ፡ ዕጣ ፡
፲፬ ተጣጣሉ ። በምሥራቅም ፡ በኩል ፡ ዕጣ ፡ ለሰ
ሌምያ ፡ ወደቀ ። ለልጁም ፡ ብልህ ፡ መካር ፡
ለሆነው ፡ ለዘካርያስ ፡ ዕጣ ፡ ጣሉ ፤ ዕጣውም ፡
፲፭ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ወጣ ። ለዖቤድኤዶም ፡ በደ
ቡብ ፡ በኩል ፥ ለልጆቹም ፡ ለዕቃ ፡ ቤቱ ፡ ዕጣ ፡
፲፮ ወጣ ። ለሰፊንና ፡ ለሖሳ ፡ በምዕራብ ፡ በኩል ፥
በዐቀበቱም ፡ መንገድ ፡ ባለው ፡ በሽሌኬት ፡
በር ፡ በኩል ፡ ጥበቃ ፡ ከጥበቃ ፡ ላይ ፡ ዕጣ ፡
፲፯ ወጣ ። በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ስድስት ፡ ሌዋው
ያን ፡ ነበሩ ፤ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ለየዕለቱ ፡ አራት ፥
በደቡብ ፡ በኩል ፡ ለየዕለቱ ፡ አራት ፥ ለዕቃ ፡
፲፰ ቤቱም ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ ነበሩ ። በምዕራብ ፡
በኩል ፡ በፈርባር ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ አራት ፥
፲፱ በፈርባርም ፡ አጠገብ ፡ ሁለት ፡ ነበሩ ። ከቆሬና ፡
ከሜራሪ ፡ ልጆች ፡ የነበሩ ፡ የበረኞች ፡ ሰሞን ፡
ይህ ፡ ነበረ ።

፳ ከሌዋውያን ፡ አኪያ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
በሚሆኑ ፡ ቤተ ፡ መዛግብትና ፡ በንዋየ ፡ ቅድሳቱ ፡
፳፩ ቤተ ፡ መዛግብት ፡ ላይ ፡ ተሾሞ ፡ ነበር ። የለአዳን ፡
ልጆች ፤ ለለአዳን ፡ የሆኑ ፡ የጌድሶናውያን ፡
ልጆች ፥ ለጌድሶናዊ ፡ ለለአዳን ፡ የሆኑ ፡ የአባ
፳፪ ቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ይሒኤሊ ፤ የይሒኤሊ ፡
ልጆች ፤ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በሚሆኑ ፡ ቤተ ፡
መዛግብት ፡ ላይ ፡ የነበሩ ፡ ዜቶም ፥ ወንድሙም ፡
፳፫ ኢዩኤል ። ከእንበረማውያን ፥ ከይስዓራው
ያን ፥ ከኬብሮናውያን ፥ ከዑዝኤላውያን ፤
፳፬ የሙሴ ፡ ልጅ ፡ የጌርሳም ፡ ልጅ ፡ ሱባኤል ፡
፳፭ በቤተ ፡ መዛግብት ፡ ላይ ፡ ተሾሞ ፡ ነበር ። ወን
ድሞቹም ፤ ከአልዓዛር ፡ ልጁ ፡ ረዓብያ ፥ ልጁም ፡
የሻያ ፥ ልጁም ፡ ኢዮራም ፥ ልጁም ፡ ዝክሪ ፥
፳፮ ልጁም ፡ ሰሎሚት ፡ መጡ ። ይህ ፡ ሰሎሚትና ፡ ወን
ድሞቹ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊትና ፡ የአባቶች ፡ ቤቶች ፡
አለቆች ፥ ሻለቆችና ፡ የመቶ ፡ አለቆች ፡ የሠራዊ
ቱም ፡ አለቆች ፥ በቀደሱት ፡ በንዋየ ፡ ቅድሳቱ ፡
ቤተ ፡ መዛግብት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ተሾመው ፡ ነበር ።
፳፯ በሰልፍም ፡ ከተገኘው ፡ ምርኮ ፡ የእግዚአብሔ
፳፰ ርን ፡ ቤት ፡ ለማበጀት ፡ ቀደሱ ። ባለ ፡ ራእዩም ፡
ሳሙኤል ፥ የቂስም ፡ ልጅ ፡ ሳኦል ፥ የኔርም ፡
ልጅ ፡ አበኔር ፥ የጽሩያም ፡ ልጅ ፡ ኢዮአብ ፡
የቀደሱት ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳት ፡ ሁሉ ፡ ከሰሎሚ
ትና ፡ ከወንድሞቹ ፡ እጅ ፡ በታች ፡ ነበረ ።

፳፱ ከይስዓራውያን ፡ ክናንያና ፡ ልጆቹ ፡ ሹማም
ትና ፡ ፈራጆች ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ በውጭው ፡
ሥራ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ተሾመው ፡ ነበር ።
፴ ከኬብሮናውያን ፡ ሐሸብያና ፡ ወንድሞቹ ፥ ጽኑ
ዓን ፡ የነበሩት ፡ ሺህ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፥
ለእግዚአብሔር ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ለንጉሥም ፡
አገልግሎት ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በምዕራብ
በኩል ፡ ባለው ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ተሾመው ፡
፴፩ ነበር ። ከኬብሮናውያንም ፡ እንደ ፡ አባቶች ፡
ቤቶች ፡ ትውልዶች ፡ የኬብሮናውያን ፡ አለቃ ፡
ይሪያ ፡ ነበረ ። ዳዊት ፡ በነገሠ ፡ በአርባኛው ፡
ዓመት ፡ ይፈልጉአቸው ፡ ነበር ፤ በእነርሱም ፡
መካከል ፡ በገለዓድ ፡ ኢያዜር ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡
፴፪ ሰዎች ፡ ተገኙ ፤ ወንድሞቹም ፡ ጽኑዓን ፡ የነበ
ሩት ፡ የአባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ሁለት ፡
ሺህ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ። ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ጉዳይ ፡ ሁሉና ፡ ለንጉሡ ፡
ጉዳይ ፡ በሮቤላውያንና ፡ በጋዳውያን ፡ በምና
ሴም ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ላይ ፡ ሹሞች ፡ አደረጋ
ቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ የአባቶች ፡ ቤቶች ፡
አለቆችና ፡ የሺህ ፡ አለቆች ፡ የመቶ ፡ አለቆ
ችም ፡ በክፍሎች ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ንጉሡን ፡ ያገ
ለገሉትም ፡ ሹማምት ፡ እንደ ፡ ቍጥራቸው ፡
እነዚህ ፡ ነበሩ ። እነዚህም ፡ ክፍሎች ፡ እያንዳ
ንዳቸው ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ሆነው ፡ በዓመት
ወራት ፡ ሁሉ ፡ በየወሩ ፡ ይገቡና ፡ ይወጡ ፡
፪ ነበር ። ለመጀመሪያው ፡ ወር ፡ በአንደኛው ፡
ክፍል ፡ ላይ ፡ የዘብድኤል ፡ ልጅ ፡ ያሾብዓም ፡
ነበረ ፤ በእርሱም ፡ ክፍል ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡
፫ ጭፍራ ፡ ነበረ ። እርሱ ፡ ከፋሬስ ፡ ልጆች ፡ ነበረ ፤
ለመጀመሪያው ፡ ወር ፡ በጭፍራ ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡
፬ ላይ ፡ ተሾሞ ፡ ነበር ። በሁለተኛውም ፡ ወር ፡
ክፍል ፡ ላይ ፡ አሆሃዊው ፡ ዱዲ ፡ ነበረ ፤ በእርሱም ፡
፭ ክፍል ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ጭፍራ ፡ ነበረ ። ለሦ
ስተኛው ፡ ወር ፡ ሦስተኛው ፡ የጭፍራ ፡ አለቃ
የካህኑ ፡ የዮዳሄ ፡ ልጅ ፡ በናያስ ፡ ነበረ ፤ በእር
ሱም ፡ ክፍል ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ጭፍራ ፡ ነበረ ።
፮ ይህ ፡ በናያስ ፡ በሠላሳው ፡ መካከል ፡ ኃያል ፡
ሆኖ ፡ በሠላሳው ፡ ላይ ፡ ነበረ ፤ በእርሱም ፡ ክፍል ፡
፯ ልጁ ፡ ዓሚዛባድ ፡ ነበረ ። ለአራተኛው ፡ ወር ፡
አራተኛው ፡ አለቃ ፡ የኢዮአብ ፡ ወንድም ፡ አሣ
ሄል ፥ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ልጁ ፡ ዝባድያ ፡ ነበረ ፤
በእርሱም ፡ ክፍል ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ጭፍራ ፡
፰ ነበረ ። ለአምስተኛው ፡ ወር ፡ አምስተኛው ፡
አለቃ ፡ ይዝራዊው ፡ ሽምሁት ፡ ነበረ ፤ በእር
ሱም ፡ ክፍል ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ጭፍራ ፡
፱ ነበረ ። ለስድስተኛው ፡ ወር ፡ ስድስተኛው ፡
አለቃ ፡ የቴቁሐዊው ፡ የዒስካ ፡ ልጅ ፡ ዒራስ ፡
ነበረ ፤ በእርሱም ፡ ክፍል ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡
፲ ጭፍራ ፡ ነበረ ። ለሰባተኛው ፡ ወር ፡ ሰባት
ኛው ፡ አለቃ ፡ ከኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ የሆነ ፡
ፍሎናዊው ፡ ሴሌስ ፡ ነበረ ፤ በእርሱም ፡ ክፍል ፡
፲፩ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ጭፍራ ፡ ነበረ ። ለስምንት
ኛው ፡ ወር ፡ ስምንተኛው ፡ አለቃ ፡ ከዛራው

ያን ፡ የነበረው ፡ ኩሳታዊው ፡ ሲቦካይ ፡ ነበረ ፤
በእርሱም ፡ ክፍል ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ጭፍራ ፡
፲፪ ነበረ ። ለዘጠኝኛው ፡ ወር ፡ ዘጠኝኛው ፡ አለቃ ፡
ከብንያማውያን ፡ የነበረው ፡ ዓናቶታዊው ፡ አቢ
ዔዜር ፡ ነበረ ፤ በእርሱም ፡ ክፍል ፡ ሀያ ፡ አራት ፡
፲፫ ሺህ ፡ ጭፍራ ፡ ነበረ ። ለአሥረኛው ፡ ወር ፡
አሥረኛው ፡ አለቃ ፡ ከዛራውያን ፡ የነበረው ፡
ነጦፋዊው ፡ ኖኤሬ ፡ ነበረ ፤ በእርሱም ፡ ክፍል ፡
፲፬ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ጭፍራ ፡ ነበረ ። ለአሥራ ፡
አንደኛው ፡ ወር ፡ አሥራ ፡ አንደኛው ፡ አለቃ ፡
ከኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ የነበረው ፡ ጲርዓቶናዊው ፡
በናያስ ፡ ነበረ ፤ በእርሱም ፡ ክፍል ፡ ሀያ ፡ አራት ፡
፲፭ ሺህ ፡ ጭፍራ ፡ ነበረ ። ለአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡
ወር ፡ አሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ አለቃ ፡ ከጎቶን
ያል ፡ ወገን ፡ የነበረው ፡ ነጦፋዊው ፡ ሔልዳይ ፡
ነበረ ፤ በእርሱም ፡ ክፍል ፡ ሀያ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡
ጭፍራ ፡ ነበረ ።

፲፮ በእስራኤልም ፡ ነገዶች ፡ ላይ ፡ እነዚህ ፡ ነበሩ ፡
በሮቤላውያን ፡ ላይ ፡ የዝክሪ ፡ ልጅ ፡ አልዓዛር ፡
አለቃ ፡ ነበረ ፤ በስምዖናውያን ፡ ላይ ፡ የመዓካ ፡
፲፯ ልጅ ፡ ሰፋጥያስ ፤ በሌዊ ፡ ላይ ፡ የቀሙኤል ፡
፲፰ ልጅ ፡ ሐሸብያ ፤ በአሮን ፡ ላይ ፡ ሳዶቅ ፤ በይ
ሁዳ ፡ ላይ ፡ ከዳዊት ፡ ወንድሞች ፡ ኤሊሁ ፤ በይ
፲፱ ሳኮር ፡ ላይ ፡ የሚካኤል ፡ ልጅ ፡ ዖምሪ ፤ በዛ
ብሎን ፡ ላይ ፡ የአብድዩ ፡ ልጅ ፡ ይሽማያ ፤ በን
ፍታሌም ፡ ላይ ፡ የዓዝሪኤል ፡ ልጅ ፡ ኢያሪ
፳ ሙት ፤ በኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ የዓዛዝያ ፡
ልጅ ፡ ሆሴዕ ፤ በምናሴ ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ላይ ፡
፳፩ የፈዳያ ፡ ልጅ ፡ ኢዩኤል ፤ በገለዓድ ፡ ባለው ፡
በምናሴ ፡ ነገድ ፡ እኩሌታ ፡ ላይ ፡ የዘካርያስ ፡
ልጅ ፡ አዶ ፤ በብንያም ፡ ላይ ፡ የአበኔር ፡ ልጅ ፡
፳፪ የዕሢኤል ፤ በዳን ፡ ላይ ፡ የይሮሐም ፡ ልጅ ፡
ዓዛርኤል ፤ እነዚህ ፡ የእስራኤል ፡ ነገዶች ፡ አለ
፳፫ ቆች ፡ ነበሩ ። እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ እስራኤ
ልን ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከዋክብት ፡ ያበዛ ፡ ዘንድ ፡
ተናግሮ ፡ ነበርና ፡ ዳዊት ፡ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ በታች ፡
፳፬ የነበሩትን ፡ አልቈጠረም ። የጽሩያ ፡ ልጅ ፡
ኢዮአብ ፡ መቍጠር ፡ ጀመረ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አል
ፈጸመም ፤ ስለዚህም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ቍጣ ፡
ሆነ ፥ ቍጥራቸውም ፡ በንጉሡ ፡ በዳዊት ፡ መዝ
ገብ ፡ አልተጻፈም ።

፳፭ በንጉሡም ፡ ቤተ ፡ መዛግብት ፡ ላይ ፡ የዓዲ
ኤል ፡ ልጅ ፡ ዓዝሞት ፡ ሹም ፡ ነበረ ፤ በሜዳ
ውም ፡ በከተሞችም ፡ በመንደሮችም ፡ በግንብ
ችም ፡ ቤተ ፡ መዛግብት ፡ ላይ ፡ የዖዝያ ፡ ልጅ ፡
፳፮ ዮናታን ፡ ሹም ፡ ነበረ ፤ መሬቱን ፡ በሚያበ
ጃጁትና ፡ እርሻውን ፡ በሚያርሱት ፡ ላይ ፡ የክ
፳፯ ሉብ ፡ ልጅ ፡ ዔዝሪ ፡ ሹም ፡ ነበረ ፤ በወይንም ፡
ቦታዎች ፡ ላይ ፡ ራማታዊው ፡ ሰሜኢ ፡ ሹም ፡
ነበረ ፤ ለወይንም ፡ ጠጅ ፡ ዕቃ ፡ ቤት ፡ በሚሆ
ነው ፡ በወይኑ ፡ ሰብል ፡ ላይ ፡ ሸፋማዊው ፡
፳፰ ዘብዲ ፡ ሹም ፡ ነበረ ፤ በቈላውም ፡ ውስጥ ፡
ባሉት ፡ በወይራውና ፡ በሾላው ፡ ዛፎች ፡ ላይ ፡
ጌድራዊው ፡ በአልሐናን ፡ ሹም ፡ ነበረ ፤ በዘይ
ቱም ፡ ቤቶች ፡ ላይ ፡ ኢዮአስ ፡ ሹም ፡ ነበረ ፤
፳፱ በሳሮንም ፡ በሚሰማሩ ፡ ከብቶች ፡ ላይ ፡ ሳሮና
ዊው ፡ ሰጥራይ ፡ ሹም ፡ ነበረ ፤ በሸለቆቹም ፡
ውስጥ ፡ በነበሩት ፡ ከብቶች ፡ ላይ ፡ የዓድላይ ፡
፴ ልጅ ፡ ሻፋጥ ፡ ሹም ፡ ነበረ ፤ በግመሎችም ፡
ላይ ፡ እስማኤላዊው ፡ ኡቢያስ ፡ ሹም ፡ ነበረ ፤
በአህዮቹም ፡ ላይ ፡ ሜሮኖታዊው ፡ ዬሕድያ ፡
፴፩ ሹም ፡ ነበረ ፤ በመንጎቹም ፡ ላይ ፡ አጋራዊው ፡
ያዚዝ ፡ ሹም ፡ ነበረ ። እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ በንጉሡ ፡
በዳዊት ፡ ሀብት ፡ ላይ ፡ ሹሞች ፡ ነበሩ ።
፴፪ አስተዋይና ፡ ጸሐፊ ፡ የነበረው ፡ የዳዊት ፡
አጐት ፡ ዮናታን ፡ አማካሪ ፡ ነበረ ፤ የሐክሞ
ኒም ፡ ልጅ ፡ ይሒኤል ፡ ከንጉሡ ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡
፴፫ ነበረ ፤ አኪጦፌልም ፡ የንጉሡ ፡ አማካሪ ፡ ነበረ ፤
አርካዊውም ፡ ኩሲ ፡ የንጉሡ ፡ ወዳጅ ፡ ነበረ ፤
፴፬ ከአኪጦፌልም ፡ ቀጥሎ ፡ የበናያስ ፡ ልጅ ፡ ዮዳ
ሄና ፡ አብያታር ፡ ነበሩ ፤ ኢዮአብም ፡ የንጉሡ ፡
ሠራዊት ፡ አለቃ ፡ ነበረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

፩ ዳዊትም ፡ የእስራኤልን ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፥
የነገዶቹንም ፡ አለቆች ፥ ንጉሡንም ፡ በክፍል ፡
የሚያገለግሉትን ፡ የጭፍሮች ፡ አለቆች ፥ ሻለ
ቆቹንም ፥ የመቶ ፡ አለቆችንም ፥ በንጉሥና ፡
በልጆች ፡ ሀብትና ፡ ግዛት ፡ ላይ ፡ የተሾሙትን ፥
ጃንደረቦችንም ፥ ጽኑዓን ፡ ኃያላኑንም ፡ ሁሉ ፡
፪ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሰበሰበ ። ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡
በእግሩ ፡ ቆሞ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ወንድሞቼና ፡
ሕዝቤ ፡ ሆይ ፥ ስሙኝ ፤ ለእግዚአብሔር ፡ ለቃል ፡
ኪዳኑ ፡ ታቦትና ፡ ለአምላካችን ፡ እግር ፡ ማረ
ፊያ ፡ የዕረፍት ፡ ቤት ፡ ለመሥራት ፡ እኔ ፡ በልቤ ፡
አስቤአለሁ ፤ ለሥራም ፡ የሚያስፈልገውን ፡
፫ አዘጋጅቻለሁ ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡— የሰ
ልፍ ፡ ሰው ፡ ነህና ፥ ደምም ፡ አፍስሰሃልና ፡
፬ ለስሜ ፡ ቤት ፡ አትሠራም ፡ ብሎኛል ። ነገር ፡
ግን ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ የዘላለም ፡ ንጉሥ ፡ እሆን ፡
ዘንድ ፡ ከአባቴ ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ መርጦኛል ፤ ይሁ
ዳንም ፡ አለቃ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ መርጦታል ፤
ከይሁዳም ፡ ቤት ፡ የአባቴን ፡ ቤት ፡ መርጦአል ፤
ከአባቴም ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ በእስራኤል ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያነግሠኝ ፡ ዘንድ ፡ ሊመርጠኝ ፡
፭ ወደደ ። እግዚአብሔርም ፡ ብዙ ፡ ልጆች ፡ ሰጥ
ቶኛልና ፡ ከልጆቼ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡
መንግሥት ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ በእስራ
ኤል ፡ ላይ ፡ ይነግሥ ፡ ዘንድ ፡ ልጄን ፡ ሰሎሞንን ፡
፮ መርጦታል ። እርሱም ፡— ልጅ ፡ ይሆነኝ ፡ ዘንድ ፡
መርጨዋለሁና ፥ እኔም ፡ አባት ፡ እሆነዋለሁና ፡
ልጅህ ፡ ሰሎሞን ፡ ቤቴንና ፡ አደባባዮቼን ፡ ይሠ
፯ ራል ። ትእዛዜንና ፡ ፍርዴንም ፡ በማድረግ ፡
እንደ ፡ ዛሬው ፡ ቢጸና ፡ መንግሥቱን ፡ ለዘላለም ፡
፰ አጸናዋለሁ ፡ አለኝ ። አሁንም ፡ የእግዚአብሔር ፡
ጉባኤ ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ እያዩ ፥ አምላካች
ንም ፡ እየሰማ ፥ ይህችን ፡ መልካሚቱን ፡ ምድር ፡

ትወርሱ ፡ ዘንድ ፥ ለልጆቻችሁም ፡ ለዘላለም ፡
ታወርሱአት ፡ ዘንድ ፡ የአምላካችሁን ፡ የእግዚ
አብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ጠብቁ ፥ ፈልጉም ።
፱ ፡ አንተም ፥ ልጄ ፡ ሰሎሞን ፡ ሆይ ፥ እግዚአብ
ሔር ፡ ልብን ፡ ሁሉ ፡ ይመረምራልና ፥ የነፍስ
ንም ፡ አሳብ ፡ ሁሉ ፡ ያውቃልና ፡ የአባትህን ፡
አምላክ ፡ እወቅ ፤ በፍጹም ፡ ልብና ፡ በነፍስህ ፡
ፈቃድም ፡ አምልከው ፤ ብትፈልገው ፡ ታገኘዋ
ለህ ፤ ብትተወው ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ይጥልሃል ።
፲ ፡ አሁንም ፥ እነሆ ፥ እግዚአብሔር ፡ ለመቅደስ ፡
የሚሆን ፡ ቤትን ፡ ትሠራ ፡ ዘንድ ፡ መርጦሃልና ፡
ጠንክረህ ፡ ፈጽመው ።
፲፩ ፡ ዳዊትም ፡ ለመቅደሱ ፡ ወለል ፥ ለቤቱም ፥
ለቤተ ፡ መዛግብቱም ፥ ለደርቡና ፡ ለውስጡም ፡
ጓዳዎች ፥ ለስርየቱም ፡ መክደኛ ፡ መቀመጫ ፡
፲፪ ፡ ምሳሌውን ፡ ለልጁ ፡ ለሰሎሞን ፡ ሰጠው ። ደግ
ሞም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አደባባዮችና ፡
በዙሪያው ፡ ለሚሆኑ ፡ ጓዳዎች ፥ ለእግዚአብሔ
ርም ፡ ቤት ፡ ለሚሆኑ ፡ ቤተ ፡ መዛግብት ፥ ለን
ዋየ ፡ ቅድሳቱም ፡ ለሚሆኑ ፡ ቤተ ፡ መዛግብት ፡
በመንፈሱ ፡ ላሰበው ፡ ሁሉ ፡ ምሳሌን ፡ ሰጠው ።
፲፫ ፡ ፲፬ ፡ የካህናቱንና ፡ የሌዋውያኑንም ፡ ክፍላቸውን ፡
በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ለሚያገለግሉበት ፡
ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አስታወቀው ። በእግዚአብሔርም ፡
ቤት ፡ ለሚያገለግሉበት ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፥ ለአገል
ግሎት ፡ ሁሉ ፡ ለሚሆነውም ፡ ለወርቁ ፡ ዕቃ ፡
ወርቁን ፡ በሚዛን ፡ ሰጠው ፤ ለአገልግሎት ፡
ሁሉ ፡ ለሚሆነውም ፡ ለብር ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ብሩን ፡
፲፭ ፡ በሚዛን ፡ ሰጠው ፤ ለወርቁም ፡ መቅረዞችና ፡ ለቀ
ንዲሎችም ፡ ወርቁን ፡ በየመቅረዙና ፡ በየቀን
ዲሉ ፡ በሚዛን ፡ ሰጠው ፤ ለብሩም ፡ መቅረዞች ፡
እንደ ፡ መቅረዙ ፡ ሁሉ ፡ ሥራ ፡ ብሩን ፡ በየመ
፲፮ ፡ ቅረዙና ፡ በየቀንዲሉ ፡ በሚዛን ፡ ሰጠው ፤ ለገጹ ፡
ኅብስት ፡ ገበታዎች ፡ ወርቁን ፡ በሚዛን ፡ ለገበ
ታዎቹ ፡ ሁሉ ፥ ብሩንም ፡ ለብሩ ፡ ገበታዎች ፡
፲፯ ፡ ሰጠው ፤ ለሜንጦቹና ፡ ለድስቶቹ ፡ ለመቅጃዎ
ቹም ፡ ጥሩውን ፡ ወርቅ ፥ ለወርቁም ፡ ጽዋዎች ፡
ወርቁን ፡ በየጽዋው ፡ ሁሉ ፡ በሚዛን ፥ ለብሩም ፡
ጽዋዎች ፡ ብሩን ፡ በየጽዋው ፡ ሁሉ ፡ በሚዛን ፡
፲፰ ፡ ሰጠው ፤ ለዕጣኑም ፡ መሠዊያ ፡ ጥሩውን ፡
ወርቅ ፡ በሚዛን ፥ ክንፎቻቸውንም ፡ ዘርግተው ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ የሸ
ፈኑትን ፡ የኪሩቤልን ፡ የወርቅ ፡ ሰረገላ ፡ ምሳሌ ፡
፲፱ ፡ ሰጠው ። ዳዊትም ፡— የሥራውን ፡ ሁሉ ፡ ምሳሌ ፡
አውቅ ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡
እጅ ፡ ተጽፎ ፡ መጣልኝ ፡ አለ ።
፳ ፡ ዳዊትም ፡ ልጁን ፡ ሰሎሞንን ፡— ጠንክር ፥
አይዞህ ፥ አድርገውም ፤ አምላኬ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ አምላክ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነውና ፡ አት
ፍራ ፥ አትደንግጥም ፤ ለእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡
አገልግሎት ፡ የሚሆነው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እስኪ
ፈጸም ፡ ድረስ ፡ እርሱ ፡ አይተውህም ፥ አይጥ
፳፩ ፡ ልህምም ። እነሆም ፥ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
አገልግሎት ፡ ሁሉ ፡ የሚሆኑ ፡ የካህናትና ፡ የሌ
ዋውያን ፡ ክፍሎች ፡ በዚህ ፡ አሉ ፤ ለሁሉም ፡
ዓይነት ፡ አገልግሎትና ፡ ሥራ ፡ በብልሃትና ፡
በነፍሱ ፡ ፈቃድ ፡ የሚሠራ ፡ ሁሉ ፡ ከአንተ ፡
ጋር ፡ ይሆናል ፤ አለቆችና ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡
ፈጽመው ፡ ይታዘዙሃል ፡ አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

፩ ፡ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ለጉባኤው ፡ ሁሉ ፡ እን
ዲህ ፡ አለ ፡— እግዚአብሔር ፡ ብቻውን ፡ የመረ
ጠው ፡ ልጄ ፡ ሰሎሞን ፡ ገና ፡ ብላቴና ፡ ለጋ ፡
ነው ፤ ሕንጻው ፡ ግን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለአ
ምላክ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ለሰው ፡ አይደለምና ፡
ሥራው ፡ ታላቅ ፡ ነው ። እኔም ፡ እንደ ፡ ጕል
፪ ፡ በቴ ፡ ሁሉ ፡ ለአምላኬ ፡ ቤት ፡ ለወርቁ ፡ ዕቃ ፡
ወርቁን ፥ ለብሩም ፡ ዕቃ ፡ ብሩን ፥ ለናሱም ፡ ዕቃ ፡
ናሱን ፥ ለብረቱም ፡ ዕቃ ፡ ብረቱን ፥ ለእንጨ
ቱም ፡ ዕቃ ፡ እንጨቱን ፥ ደግሞም ፡ መረግድ
ንና ፡ በፈርጥ ፡ የሚገባ ፡ ድንጋይን ፥ የሚለጠፍ ፡
ድንጋይን ፥ ልዩ ፡ ልዩ ፡ መልክ ፡ ያለውንም ፡
ድንጋይ ፥ የከበረውንም ፡ ድንጋይ ፡ ከየዓይነቱ ፥
ብዙም ፡ እብነ ፡ በረድ ፡ አዘጋጅቻለሁ ። ከዚ
፫ ፡ ህም ፡ በላይ ፡ ደግሞ ፡ የአምላኬን ፡ ቤት ፡ ስለ ፡
ወደድሁ ፥ ለመቅደሱ ፡ ካዘጋጀሁት ፡ ሁሉ ፡ ሌላ ፡
የግል ፡ ገንዘቤ ፡ የሚሆን ፡ ወርቅና ፡ ብር ፡ አለ
ኝና ፡ ለአምላኬ ፡ ቤት ፡ ሰጥቼዋለሁ ። የቤቶቹ ፡
፬ ፡ ግንብ ፡ ይለበጡበት ፡ ዘንድ ፡ ከኦፊር ፡ ወርቅ ፡
ሦስት ፡ ሺህ ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፥ ሰባት ፡ ሺህም ፡
መክሊት ፡ ጥሩ ፡ ብር ፥ በሠራተኞች ፡ እጅ ፡
፭ ፡ ለሚሠራው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ለወርቁ ፡ ዕቃ ፡ ወር
ቁን ፥ ለብሩም ፡ ዕቃ ፡ ብሩን ፡ ሰጥቻለሁ ። ዛሬ ፤
በፈቃዱ ፡ ራሱን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቀድስ ፡
ማን ፡ ነው ?
፮ ፡ የአባቶችም ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፥ የእስራኤ
ልም ፡ ነገዶች ፡ አለቆች ፥ ሻለቆችም ፥ የመቶ ፡
አለቆችም ፥ በንጉሡም ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ የተሾ
፯ ፡ ሙት ፡ በፈቃዳቸው ፡ አቀረቡ ። ለእግዚአብ
ሔርም ፡ ቤት ፡ አገልግሎት ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡
መክሊት ፡ ወርቅና ፡ እሥር ፡ ሺህ ፡ ዳሪክ ፥
እሥር ፡ ሺህም ፡ መክሊት ፡ ብር ፥ አሥራ ፡ ስም
ንት ፡ ሺህም ፡ መክሊት ፡ ናስ ፥ መቶ ፡ ሺህም ፡
፰ ፡ መክሊት ፡ ብረት ፡ ሰጡ ። ዕንቍም ፡ ያለው ፡
ሰው ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ለሆነው ፡
ቤተ ፡ መዛግብት ፡ በጌድሶናዊው ፡ በይሒኤል ፡
፱ ፡ እጅ ፡ ሰጠ ። ሕዝቡም ፡ ፈቅደው ፡ ሰጥተዋ
ልና ፥ በፍጹም ፡ ልባቸውም ፡ ለእግዚአብሔር ፡
በፈቃዳቸው ፡ አቅርበዋልና ፡ ደስ ፡ አላቸው ፤
ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ደግሞ ፡ ታላቅ ፡ ደስታ ፡ ደስ ፡
አለው ።
፲ ፡ ዳዊትም ፡ በጉባኤው ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ ባረከ ፤ ዳዊትም ፡ አለ ፡— አቤቱ ፥ የአ
ባታችን ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ ከዘላ
፲፩ ፡ ለም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ተባረክ ። አቤቱ ፥ በሰማ
ይና ፡ በምድር ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ የአንተ ፡ ነውና ፡
ታላቅነትና ፡ ኃይል ፥ ክብርም ፥ ድልና ፡ ግርማ ፡

ለአንተ ፡ ነው ፤ አቤቱ ÷ መንግሥት ፡ የአንተ ፡
ነው ÷ አንተም ፡ በሁሉ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያልህ ፡
፲፪ ራስ ፡ ነህ ። ባለጠግነትና ፡ ክብር ፡ ከአንተ ፡
ዘንድ ፡ ነው ÷ አንተም ፡ ሁሉን ፡ ትገዛለህ ፤
ኀይልና ፡ ብርታት ፡ በእጅህ ፡ ነው ፤ ታላቅ ፡
ለማድረግ ÷ ለሁሉም ፡ ኀይልን ፡ ለመስጠት ፡
፲፫ በእጅህ ፡ ነው ። አሁንም ፡ እንግዲህ ÷ አምላክ
ችን ፡ ሆይ ÷ እንገዛልሃለን ÷ ለክቡር ፡ ስምህም ፡
፲፬ ምስጋና ፡ እናቀርባለን ። ሁሉ ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡
ነውና ÷ ከእጅህም ፡ የተቀበልነውን ፡ ሰጥተን
ሃልና ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ችለን ፡ ልናቀርብልህ ፡
፲፭ እኔ ፡ ማን ፡ ነኝ ? ሕዝቤስ ፡ ማን ፡ ነው ? አባ
ቶቻችንም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ እኛ ፡ በፊ
ትህ ፡ ስደተኞችና ፡ መጻተኞች ፡ ነን ፤ ዘመናች
ንም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ናት ÷ አት
፲፮ ጸናም ። አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ሆይ ÷ ለቅዱስ ፡
ስምህ ፡ ቤት ፡ እንሠራ ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ያዘጋጀ
ነው ፡ ባለጠግነት ፡ ሁሉ ፡ ከእጅህ ፡ የመጣ ፡
፲፯ ነው ÷ ሁሉም ፡ የአንተ ፡ ነው ። አምላኬ ፡ ሆይ ÷
ልብን ፡ እንድትመረምር ÷ ቅንነትንም ፡ እንድ
ትወድድ ፡ አውቃለሁ ፤ እኔም ፡ በልቤ ፡ ቅንነ
ትና ፡ በፈቃዴ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ አቅርቤአለሁ ፤
አሁንም ፡ በዚህ ፡ ያለው ፡ ሕዝብህ ፡ በፈቃዱ ፡
፲፰ እንዳቀረበልህ ፡ በደስታ ፡ አይቻለሁ ። አቤቱ ÷
የአባቶቻችን ፡ የአብርሃምና ፡ የይስሐቅ ፡ የእስ
ራኤልም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ ይህን ፡ አሳብ ፡ በሕ
ዝብህ ፡ ልብ ፡ ለዘላለም ፡ ጠብቅ ÷ ልባቸውንም ፡
፲፱ ወደ ፡ አንተ ፡ አቅና ። ትእዛዝህንም ፡ ምስክር
ህንም ፡ ሥርዓትህንም ፡ ይጠብቅ ፡ ዘንድ ÷ ይህ
ንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ÷ ያዘጋጀሁ
ለትንም ፡ ቤት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ለልጄ ፡ ለሰሎ
ሞን ፡ ፍጹም ፡ ልብ ፡ ስጠው ።
፳ ዳዊትም ፡ ጉባኤውን ፡ ሁሉ ፡— አምላካች
ሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩ ፡ አላቸው ። ጉባ
ኤውም ፡ ሁሉ ፡ የአባታቸውን ፡ አምላክ ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ ባረኩ ÷ ራሳቸውንም ፡ አዘንብ
ለው ፡ ለእግዚአብሔርና ፡ ለንጉሡ ፡ ሰገዱ ።
፳፩ በነጋውም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሥዋዕት ፡
ሠዉ ÷ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ አቀረቡ ፤ አንድ ፡ ሺህ ፡ ወይፈን ÷
አንድ ፡ ሺህም ፡ አውራ ፡ በጎች ÷ አንድ ፡ ሺህም ፡
የበግ ፡ ጠቦቶች ÷ የመጠጥ ፡ ቍርባናቸውንም ÷
ስለ ፡ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ብዙ ፡ መሥዋዕት ፡
፳፪ አቀረቡ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ በታላቅ ፡ ደስታ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በሉ ፡ ጠጡም ። የዳ
ዊትንም ፡ ልጅ ፡ ሰሎሞንን ፡ ሁለተኛ ፡ ጊዜ ፡
አነገሡት ፤ እርሱንም ፡ አለቃ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ቀቡት ÷ ሳዶቅንም ፡ ካህን ፡
፳፫ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ቀቡት ። ሰሎሞንም ፡ በአባቱ ፡
በዳዊት ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ÷ ተከናወነለ
፳፬ ትም ፤ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ታዘዙለት ። አለ
ቆቹም ፡ ሁሉ ÷ ኀያላኑም ÷ ደግሞም ፡ የንጉሡ ፡
የዳዊት ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ለንጉሡ ፡ ለሰሎሞን ፡
፳፭ እጅ ፡ ሰጡት ። እግዚአብሔርም ፡ ሰሎሞንን ፡
በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ እጅግ ፡ አገነነው ፤ ከእ
ርሱ ፡ በፊትም ፡ ለነበሩት ፡ ለእስራኤል ፡ ነገሥ
ታት ፡ ያልሆነውን ፡ የመንግሥት ፡ ክብር ፡ ሰጠው ።
፳፮ የእሴይም ፡ ልጅ ፡ ዳዊት ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡
፳፯ ላይ ፡ ነገሠ ። በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ የነገሠበት ፡
ዘመን ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ነበረ ፤ ሰባት ፡ ዓመት ፡
በኬብሮን ፡ ነገሠ ÷ ሠላሳ ፡ ሦስትም ፡ ዓመት ፡
፳፰ በኢየሩሳሌም ፡ ነገሠ ። ዕድሜም ÷ ባለጠግነ
ትም ÷ ክብርም ፡ ጠግቦ ፡ በመልካም ፡ ሽምግ
ልና ፡ ሞተ ፤ ልጁም ፡ ሰሎሞን ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡
፳፱ ነገሠ ። የንጉሡም ፡ የዳዊት ፡ የፊተኛውና ፡ የኋ
ለኛው ፡ ነገር ÷ እነሆ ÷ በባለ ፡ ራእዩ ፡ በሳሙ
ኤል ፡ ታሪክ ÷ በነቢዩም ፡ በናታን ፡ ታሪክ ÷
በባለ ፡ ራእዩም ፡ በጋድ ፡ ታሪክ ፡ ተጽፎአል ።
፴ እንደዚሁም ፡ የመንግሥቱ ፡ ነገርና ፡ ኀይሉ ፡
ሁሉ ፡ በእርሱም ፡ በእስራኤልም ፡ በአገሮችም ፡
መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያለፉት ፡ ዘመናት ፡
ተጽፈዋል ።

# መጽሐፈ ፡ ዜና ፡ መዋዕል ፡ ካልዕ ።

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ ሰሎሞንም ፡ በመንግሥቱ ፡
በረታ ፤ አምላኩም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእርሱ ፡
፪ ጋር ፡ ነበረ ÷ እጅግም ፡ አገነነው ። ሰሎሞንም ፡
ለእስራኤል ፡ ሁሉ ÷ ለሻለቆች ÷ ለመቶ ፡ አለቆ
ችም ÷ ለፈራጆችም ÷ በእስራኤልም ፡ ሁሉ ፡
ዘንድ ፡ ለነበሩ ፡ መሳፍንት ፡ ሁሉ ÷ ለአባቶች ፡
፫ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ተናገረ ። ሰሎሞንም ፡ ከእር
ሱም ፡ ጋር ፡ ጉባኤው ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የሠራው ፡ የእግ
ዚአብሔር ፡ መገናኛ ፡ ድንኳን ፡ በዚያ ፡ ነበረና ፡
በገባዖን ፡ ወዳለው ፡ የኮረብታው ፡ መስገጃ ፡
ሄዱ ። ለእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ግን ፡ ዳዊት ፡
፬ በኢየሩሳሌም ፡ ድንኳን ፡ ተክሎለት ፡ ነበርና ፡
ዳዊት ፡ ከቂርያትይዓሪም ፡ ወዳዘጋጀለት ፡ ስፍራ ፡
አምጥቶት ፡ ነበር ። የሆርም ፡ ልጅ ፡ የኡሪ ፡
፭ ልጅ ፡ ባስልኤል ፡ የሠራው ፡ የናስ ፡ መሠዊያ ፡
በዚያ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ፊት ፡ ነበረ ፤
ሰሎሞንም ፡ ጉባኤውም ፡ ይህን ፡ ይፈልጉት ፡
፮ ነበር ። ሰሎሞንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
በመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ አጠገብ ፡ ወዳለው ፡
ወደ ፡ ናሱ ፡ መሠዊያ ፡ ወጣ ÷ በዚያም ፡ አንድ ፡
ሺህ ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረበ ።
፯ በዚያም ፡ ሌሊት ፡ እግዚአብሔር ፡— ምን ፡
እንድሰጥህ ፡ ለምነኝ ፡ ሲል ፡ ለሰሎሞን ፡ ተገ

፰ ለጠ ። ሰሎሞንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አለው ፡— ከአባቴ ፡ ከዳዊት ፡ ጋር ፡ ታላቅ ፡ ምሕረት ፡ አድርገሃል ÷ በእርሱም ፡ ፋንታ ፡ አንግሠኸኛል ። ፱ አሁንም ÷ አቤቱ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ ቍጥሩ ፡ እንደ ፡ ምድር ፡ ትቢያ ፡ በሆነው ፡ በብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ አንግሠኸኛልና ፡ ለአባቴ ፡ ለዳዊት ፡ የሰጠኸው ፡ ተስፋ ፡ ይጽና ። ፲ አሁንም ፡ በዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ፊት ፡ እወጣና ፡ እገባ ፡ ዘንድ ፡ ጥበብንና ፡ እውቀትን ፡ ስጠኝ ፤ ይህን ፡ በሚያህል ፡ በዚህ ፡ በታላቅ ፡ ሕዝብህ ፡ ላይ ፡ ይፈርድ ፡ ዘንድ ፡ የሚችል ፡ የለምና ። ፲፩ እግዚአብሔርም ፡ ሰሎሞንን ፡— ይህ ፡ በልብህ ፡ ነበረና ÷ ባለጠግነትንና ፡ ሀብትን ፡ ክብርንና ፡ የጠላቶችህን ፡ ነፍስ ፡ ረጅምም ፡ ዕድሜን ፡ አልለመንህምና ÷ ነገር ፡ ግን ፡ በነገሥሁህ ፡ በሕዝቤ ፡ ላይ ፡ ለመፍረድ ፡ ትችል ፡ ዘንድ ፡ ጥበብንና ፡ እውቀትን ፡ ለራስህ ፡ ለምነሃልና ፡ ፲፪ ጥበብንና ፡ እውቀትን ፡ ሰጥቼሃለሁ ፤ ከአንተ ፡ በፊትም ፡ ከነበሩት ፡ ከአንተም ፡ በኋላ ፡ ከሚነሡት ፡ ነገሥታት ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ የሚመስልህ ፡ እንዳይኖር ፡ ባለጠግነትንና ፡ ሀብትን ፡ ክብርንም ፡ እሰጥሃለሁ ፡ አለው ። ፲፫ ሰሎሞንም ፡ በገባዖን ፡ ካለው ፡ ከኮረብታው ፡ መስገጃ ፡ ከመገናኛው ፡ ድንኳን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጣ ፤ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ነገሠ ።

፲፬ ሰሎሞንም ፡ ሰረገሎችንና ፡ ፈረሰኞችን ፡ ሰበሰበ ÷ አንድ ፡ ሺህም ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሰረገሎች ÷ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህም ፡ ፈረሰኞች ፡ ነበሩት ፤ በሰረገሎች ፡ ከተሞችና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አኖራቸው ። ፲፭ ንጉሡም ፡ ብሩንና ፡ ወርቁን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ እንደ ፡ ድንጋይ ፡ እንዲበዛ ፡ አደረገው ፤ የዝግባም ፡ እንጨት ፡ ብዛት ፡ በቈላ ፡ እንደሚበቅል ፡ ሾላ ፡ ሆነ ። ፲፮ ሰሎሞንም ፡ ፈረሶችን ፡ ከግብጽና ፡ ከቀዌ ፡ አስመጣ ፤ የንጉሡም ፡ ነጋዴዎች ፡ በገንዘብ ፡ እየገዙ ፡ ከቀዌ ፡ ያመጡአቸው ፡ ነበር ። ፲፯ አንዱም ፡ ሰረገላ ፡ በስድስት ፡ መቶ ÷ አንዱም ፡ ፈረስ ፡ በመቶ ፡ አምሳ ፡ ሰቅል ፡ ብር ፡ ከግብጽ ፡ ይወጣ ፡ ነበር ፤ እንዲሁም ፡ ለኬጢያውያንና ፡ ለሶርያ ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ በእጃቸው ፡ ያመጡላቸው ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ሰሎሞንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ቤት ÷ ለመንግሥቱም ፡ ቤት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ አሰበ ። ፪ ሰሎሞንም ፡ የሚሸከሙትን ፡ ሰባ ፡ ሺህ ÷ ከተራሮችም ፡ የሚጠርቡትን ፡ ሰማንያ ፡ ሺህ ÷ በእነርሱም ፡ ላይ ፡ የተሾሙትን ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ቈጠረ ። ፫ ሰሎሞንም ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ወደ ፡ ጢሮስ ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ኪራም ፡ ላከ ፡— ከአባቴ ፡ ከዳዊት ፡ ጋር ፡ እንዳደረግህ ÷ የሚቀመጥበትንም ፡ ቤት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ የዝግባ ፡ እንጨት ፡ እንደ ፡ ሰደድህለት ÷ እንዲሁ ፡ ለእኔ ፡ አድርግ ። ፬ እነሆ ÷ ለእስራኤል ፡ ለዘላለም ፡ እንደ ፡ ታዘዘው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የጣፋጩን ፡ ሽቱ ፡ ዕጣን ፡ ለማጠን ÷ የገጹንም ፡ ኅብስት ፡ ለማኖር ÷ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ በጥዋትና ፡ በማታ ፡ በሰንበታቱም ፡ በመባቻዎቹም ፡ በአምላካችንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ በዓላት ፡ ለማቅረብ ፡ ለአምላኬ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ቤት ፡ እሠራና ፡ እቀድስ ፡ ዘንድ ፡ አሰብሁ ። ፭ አምላካችንም ፡ ከአማልክት ፡ ሁሉ ፡ በላይ ፡ ታላቅ ፡ ነውና ፡ የምሠራው ፡ ቤት ፡ ታላቅ ፡ ነው ። ፮ ነገር ፡ ግን ፡ ሰማይና ፡ ከሰማያት ፡ በላይ ፡ ያለ ፡ ሰማይ ፡ ይይዘው ፡ ዘንድ ፡ አይችልምና ፡ ለእርሱ ፡ ቤት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ማን ፡ ይችላል ? በፊቱ ፡ ዕጣን ፡ ከማጠን ፡ በቀር ፡ ቤት ፡ እሠራለት ፡ ዘንድ ፡ እኔ ፡ ማን ፡ ነኝ ? ፯ አሁንም ፡ አባቴ ፡ ዳዊት ፡ ከዘጋጃቸው ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ካሉት ፡ ብልሃተኞች ፡ ጋር ፡ የሚሆን ÷ ወርቁንና ፡ ብሩን ÷ ናሱንና ፡ ብረቱን ÷ ሐምራዊውንና ፡ ቀዩን ፡ ሰማያዊውንም ፡ ግምጃ ፡ የሚሠራ ÷ ቅርጽንም ፡ የሚያውቅ ፡ ብልሃተኛ ፡ ሰው ፡ ላክልኝ ። ፰ ደግሞም ፡ ባሪያዎችህ ፡ ከሊባኖስ ፡ እንጨት ፡ መቍረጥ ፡ እንዲያውቁ ፡ እኔ ፡ አውቃለሁና ፡ ከሊባኖስ ፡ የዝግባና ፡ የጥድ ፡ የሰንደልም ፡ እንጨት ፡ ስደድልኝ ። ፱ የምሠራውም ፡ ቤት ፡ እጅግ ፡ ታላቅና ፡ ድንቅ ፡ ይሆናልና ፡ ብዙ ፡ እንጨት ፡ ያዘጋጁልኝ ፡ ዘንድ ÷ እነሆ ÷ ባሪያዎቼ ፡ ከባሪያዎችህ ፡ ጋር ፡ ይሆናሉ ። ፲ እነሆም ÷ እንጨቱን ፡ ለሚቈርጡ ፡ ለባሪያዎችህ ፡ ሀያ ፡ ሺህ ፡ የቆሮስ ፡ መስፈሪያ ፡ የተበጠረ ፡ ስንዴ ÷ ሀያ ፡ ሺህም ፡ የቆሮስ ፡ መስፈሪያ ፡ ገብስ ÷ ሀያ ፡ ሺህም ፡ የባዶስ ፡ መስፈሪያ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ÷ ሀያ ፡ ሺህም ፡ የባዶስ ፡ መስፈሪያ ፡ ዘይት ፡ እሰጣለሁ ።

፲፩ የጢሮስ ፡ ንጉሥም ፡ ኪራም ፡— እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ ወድዶአልና ፡ በላያቸው ፡ አነገሠህ ፡ ብሎ ፡ ለሰሎሞን ፡ መልእክት ፡ ላከ ። ፲፪ ኪራምም ፡ ደግሞ ፡ አለ ፡— ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ የፈጠረ ÷ ለእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ለመንግሥቱም ፡ ቤት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ጥበበኛና ፡ ብልሃተኛ ፡ አስተዋይም ፡ ልጅ ፡ ለንጉሡ ፡ ለዳዊት ፡ የሰጠ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቡሩክ ፡ ይሁን ። ፲፫ አሁንም ፡ ከብልሃተኞችህ ፡ ጋር ፡ ከጌታዬም ፡ ከአባትህ ፡ ከዳዊት ፡ ብልሃተኞች ፡ ጋር ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ኪራምአቢ ፡ የሚባል ፡ ብልሃተኛና ፡ አስተዋይ ፡ ሰው ፡ ሰድጄልሃለሁ ። ፲፬ እናቱ ፡ ከዳን ፡ ልጆች ፡ ናት ÷ አባቱም ፡ የጢሮስ ፡ ሰው ፡ ነው ፤ ወርቁንና ፡ ብሩንም ÷ ናሱንና ፡ ብረቱን ÷ ድንጋይንና ፡ እንጨቱን ÷ ሐምራዊውንና ፡ ሰማያዊውን ፡ ቀዩንም ፡ ግምጃ ÷ ጥሩውንም ፡ በፍታ ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ÷ ቅርጽም ፡ ሌላም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ያውቃል ። ፲፭ አሁንም ፡ ጌታዬ ፡ የተናገረውን ፡ ስንዴውንና ፡ ገብሱን ፡ ዘይቱንና ፡ የወይን ፡ ጠጁን ፡ ወደ ፡ ባሪያዎቹ ፡ ይስደድ ፤ ፲፮ እኛም ፡ ከሊባኖስ ፡ የምትሻውን ፡ ያህል ፡ እንጨት ፡ እንቈርጣለን ÷ በታንኳም ፡ አድርገን ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ወደ ፡ ኢዮጴ ፡ እንሰድዳለን ፤ አንተም ፡ ወደ ፡

ኢየሩሳሌም ፡ ታስወስደዋለህ ።
፲፯ ሰሎሞንም ፡ በእስራኤል ፡ ምድር ፡ የነበሩ
ትን ፡ መጻተኞች ፡ ሁሉ ፡ አባቱ ፡ ዳዊት ፡ እንደ ፡
ቈጠራቸው ፡ ቈጠረ ፤ መቶ ፡ አምሳ ፡ ሦስት ፡
፲፰ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ተገኙ ። ከእነርሱም ፡
የሚሸከሙትን ፡ ሰባ ፡ ሺህ ፥ በተራሮችም ፡
ላይ ፡ የሚጠርቡትን ፡ ሰማንያ ፡ ሺህ ፥ በሕዝ
ቡም ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ የተሾሙትን ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡
ስድስት ፡ መቶ ፡ አደረገ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ሰሎሞንም ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአባቱ ፡ ለዳ
ዊት ፡ በተገለጠበት ፡ በሞሪያ ፡ ተራራ ፡ ዳዊት ፡
በዘጋጀው ፡ ስፍራ ፡ በኢያቡሳዊው ፡ በኦርና ፡
አውድማ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የእግዚአብሔርን ፡
፪ ቤት ፡ መሥራት ፡ ጀመረ ። በነገሡም ፡ በአራተ
ኛው ፡ ዓመት ፡ በሁለተኛው ፡ ወር ፡ መሥራት ፡
፫ ጀመረ ። ሰሎሞንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡
ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ የጣለው ፡ መሠረት ፡ ይህ ፡ ነው ፤
ርዝመቱም ፡ በዱሮው ፡ ስፍር ፡ ስድሳ ፡ ክንድ ፥
፬ ወርዱም ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። በቤቱም ፡ ፊት ፡
የነበረው ፡ ወለል ፡ ርዝመቱ ፡ እንደ ፡ ቤቱ ፡
ወርድ ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፥ ቁመቱም ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡
ክንድ ፡ ነበረ ፤ ውስጡንም ፡ በጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ለበ
፭ ጠው ። ታላቁንም ፡ ቤት ፡ በጥድ ፡ እንጨት ፡
ከደነው ፥ በጥሩም ፡ ወርቅ ፡ ለበጠው ፤ የዘንባ
፮ ባና ፡ የሰንሰለት ፡ አምሳል ፡ ቀረጸበት ። ቤቱ
ንም ፡ በዕንቍ ፡ አስጌጠው ፤ ወርቁም ፡ የፈርዋ
፯ ይም ፡ ወርቅ ፡ ነበረ ። ቤቱንም ፡ ሰረገሎቹንም ፡
መድረኮቹንም ፡ ግንቦቹንም ፡ ደጆቹንም ፡ በወ
ርቅ ፡ ለበጠ ፤ በግንቦቹም ፡ ላይ ፡ ኪሩቤልን ፡
ቀረጸ ።
፰ ቅድስተ ፡ ቅዱሳኑንም ፡ ሠራ ፤ ርዝመቱም ፡
እንደ ፡ ቤቱ ፡ ወርድ ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፥ ወርዱም ፡
ሀያ ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፤ ስድስት ፡ መቶ ፡ መክሊት ፡
፱ በሚያህል ፡ በጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ለበጠው ። የምስ
ማሮቹም ፡ ሚዛን ፡ አምሳ ፡ ሰቅል ፡ ወርቅ ፡ ነበረ ።
የደርቡንም ፡ ጓዳዎች ፡ በወርቅ ፡ ለበጠ ።
፲ በቅድስተ ፡ ቅዱሳንም ፡ ውስጥ ፡ ከእንጨት ፡
ሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ኪሩቤልን ፡ ሠራ ፥ በወርቅም ፡
፲፩ ለበጣቸው ። የኪሩቤልም ፡ ክንፎች ፡ ሀያ ፡
ክንድ ፡ ሙሉ ፡ ተዘርግተው ፡ ነበር ፤ የአንዱ ፡
ኪሩብ ፡ ክንፍ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ የቤ
ቱንም ፡ ግንብ ፡ ይነካ ፡ ነበረ ፤ ሁለተኛው ፡ ክንፍ ፡
አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ የሁለተኛውንም ፡
፲፪ ኪሩብ ፡ ክንፍ ፡ ይነካ ፡ ነበር ። የሁለተኛውም ፡
ኪሩብ ፡ ክንፍ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ የቤ
ቱንም ፡ ግንብ ፡ ይነካ ፡ ነበር ፤ ሁለተኛውም ፡
ክንፍ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ የሌላውንም ፡
፲፫ ኪሩብ ፡ ክንፍ ፡ ይነካ ፡ ነበር ። የእነዚህም ፡
ኪሩቤል ፡ ክንፎች ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፡ ሙሉ ፡ ተዘ
ርግተው ፡ ነበር ፤ በእግራቸውም ፡ ቆመው ፡
ነበር ፥ ፊቶቻቸውም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ይመለከቱ ፡
ነበር ።

፲፬ ከሰማያዊውም ፡ ከሐምራዊውም ፡ ከቀዩም ፡
ሐር ፡ ከጥሩም ፡ በፍታ ፡ መጋረጃውን ፡ ሠራ ፥
ኪሩቤልንም ፡ ጠለፈበት ።
፲፭ በቤቱም ፡ ፊት ፡ ቁመታቸው ፡ ሠላሳ ፡ አም
ስት ፡ ክንድ ፡ የነበረውን ፡ ሁለቱን ፡ ዓምዶች ፡
ሠራ ፥ በእያንዳንዳቸውም ፡ ላይ ፡ የነበረው ፡
ጕልላት ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ።
፲፮ እንደ ፡ ድሪ ፡ ያሉ ፡ ሰንሰለቶችንም ፡ ሠርቶ ፡
በአዕማዱ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ አደረጋቸው ፤ መቶም ፡
ሮማኖች ፡ ሠርቶ ፡ በሰንሰለቱ ፡ ላይ ፡ አደረጋ
፲፯ ቸው ። አዕማዶቹንም ፡ አንደኛውን ፡ በቀኝ ፥
ሁለተኛውን ፡ በግራ ፡ በመቅደሱ ፡ ፊት ፡ አቆ
ማቸው ፤ በቀኝም ፡ የነበረውን ፡ ስም ፡ ያቁም ፥
በግራም ፡ የነበረውን ፡ ስም ፡ በለዝ ፡ ብሎ ፡ ጠራ
ቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ደግሞም ፡ ርዝመቱ ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፥ ወርዱም ፡
ሀያ ፡ ክንድ ፥ ቁመቱም ፡ አሥር ፡ ክንድ ፡ የነበ
፪ ረውን ፡ የናሱን ፡ መሠዊያ ፡ ሠራ ። ከፈሰሰም ፡
ናስ ፡ ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ አሥር ፡ ክንድ ፥ ቁመ
ቱም ፡ አምስት ፡ ክንድ ፥ በዙሪያውም ፡ ሠላሳ ፡
፫ ክንድ ፡ የሆነ ፡ ክብ ፡ ኵሬ ፡ ሠራ ። በበታቹም ፡
ለአንድ ፡ ክንድ ፡ አሥር ፥ ለአንድም ፡ ክንድ ፡
አሥር ፥ ጕብጕቦች ፡ አዞረበት ፤ ኵሬውም ፡ በቀ
ለጠ ፡ ጊዜ ፡ ጕብጕቦቹ ፡ በሁለት ፡ ተራ ፡ ከእርሱ ፡
፬ ጋር ፡ አብረው ፡ ቀልጠው ፡ ነበር ። በአሥራ ፡
ሁለትም ፡ በሬዎች ፡ ምስል ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡
ነበር ፤ ከእነርሱም ፡ ሦስቱ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ሦስ
ቱም ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ሦስቱም ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡
ሦስቱም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ፤
ኵሬውም ፡ በላያቸው ፡ ነበረ ፥ የሁሉም ፡ ጀር
፭ ባቸው ፡ በስተ ፡ ውስጥ ፡ ነበረ ። ውፍረቱም ፡
አንድ ፡ ጋት ፡ ያህል ፡ ነበረ ፤ ከንፈሩም ፡
እንደ ፡ ጽዋ ፡ ከንፈር ፥ እንደ ፡ ሱፍ ፡ አበባ ፡
ሆኖ ፡ ተሠርቶ ፡ ነበር ፤ ሦስት ፡ ሺህም ፡ የባዶስ ፡
፮ መስፈሪያ ፡ ይይዝ ፡ ነበር ። ደግሞም ፡ አሥር ፡
የመታጠቢያ ፡ ሰኖች ፡ ሠራ ፥ ለሚቃጠለውም ፡
መሥዋዕት ፡ የሚቀርበው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ይታ
ጠብባቸው ፡ ዘንድ ፡ አምስቱን ፡ በቀኝ ፥ አምስ
ቱንም ፡ በግራ ፡ አኖራቸው ፤ ኵሬው ፡ ግን ፡
ካህናት ፡ ይታጠቡበት ፡ ነበር ።
፯ አሥሩንም ፡ መቅረዞች ፡ እንደ ፡ ሥርዓታ
ቸው ፡ ከወርቅ ፡ ሠርቶ ፡ አምስቱን ፡ በቀኝ ፥
አምስቱንም ፡ በግራ ፡ በመቅደሱ ፡ ውስጥ ፡ አኖ
፰ ራቸው ። አሥሩንም ፡ ገበታዎች ፡ ሠርቶ ፡ አም
ስቱን ፡ በቀኝ ፥ አምስቱንም ፡ በግራ ፡ በመቅ
ደሱ ፡ ውስጥ ፡ አኖራቸው ። አንድ ፡ መቶም ፡
፱ የወርቅ ፡ ድስቶች ፡ ሠራ ። ደግሞም ፡ የካህና
ቱን ፡ አደባባይ ፥ ታላቁንም ፡ አደባባይ ፥ የአ
ደባባዩንም ፡ ደጆች ፡ ሠራ ፥ ደጆቻቸውንም ፡
፲ በናስ ፡ ለበጠ ። ኵሬውንም ፡ በቤቱ ፡ ቀኝ ፡
በአዜብ ፡ በኩል ፡ አኖረው ።
፲፩ ኪራምም ፡ ምንቸቶቹንና ፡ መጫሪያዎቹን ፡

ድስቶቹንም ፡ ሠራ ። ኪራምም ፡ ለንጉሡ ፡
ለሰሎሞን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የሠራውን ፡
፲፪ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ጨረሰ ። ሁለቱን ፡ አዕማድ ÷
ጽዋዎቹንም ÷ በአዕማዱም ፡ ላይ ፡ የነበሩትን ፡
ሁለት ፡ ጕልላቶች ÷ በአዕማዱም ፡ ላይ ፡ የነበ
ሩትን ፡ የጕልላቶች ፡ ሁለቱን ፡ ጽዋዎች ፡ የሚ
፲፫ ሸፍኑትን ፡ ሁለቱን ፡ መርበቦች ፡ ሠራ ። በአዕ
ማዱም ፡ ላይ ፡ የነበሩትን ፡ ሁለቱን ፡ ጕልላቶች ፡
ይሸፍኑ ፡ ዘንድ ÷ ለእያንዳንዱ ፡ መርበብ ፡
ሁለት ፡ ሁለት ፡ ተራ ፡ ሮማኖች ÷ ለሁለቱ ፡ መር
በቦች ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሮማኖች ፡ አደረገ ።
፲፬ መቀመጫዎቹንና ፡ በመቀመጫዎቹ ፡ ላይ ፡ የሚ
፲፭ ቀመጡትን ፡ የመታጠቢያ ፡ ሰኖች ÷ አንዱ
ንም ፡ ኵሬ ÷ በበታቹም ፡ የሚሆኑትን ፡ አሥራ ፡
፲፮ ሁለት ፡ በሬዎች ፡ ሠራ ። ምንቸቶቹንም ፡ መጫ
ሪያዎቹንም ፡ ሜንጦቹንም ፡ ዕቃቸውንም ፡ ሁሉ ፡
ኪራም ፡ ለንጉሡ ፡ ለሰሎሞን ፡ ስለ ፡ እግዚአብ
፲፯ ሔር ፡ ቤት ፡ ከለሰላሳ ፡ ናስ ፡ ሠራ ። ንጉሡም ፡
በዮርዳኖስ ፡ ሜዳ ፡ በሱኮትና ፡ በጽሬዳ ፡ መካከል ፡
ባለው ፡ በወፍራሙ ፡ መሬት ፡ ውስጥ ፡ አስፈሰ
፲፰ ሰው ። ሰሎሞንም ፡ እነዚህን ፡ ዕቃዎች ፡ ሁሉ ፡
እጅግ ፡ አብዝቶ ፡ ሠራ ፤ የናሱም ፡ ሚዛን ፡
አይቈጠርም ፡ ነበር ።

፲፱ ሰሎሞንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የነበረ
ውን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ÷ የወርቁንም ፡ መሠዊያ ÷
የገጹም ፡ ኅብስት ፡ የነበረባቸውን ፡ ገበታዎች ÷
፳ በቅድስተ ፡ ቅዱሳንም ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ሥርዓታ
ቸው ፡ ያበሩ ፡ ዘንድ ፡ መቅረዞችንና ፡ ቀንዲሎ
፳፩ ቻቸውን ፡ ከጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ሠራ ። አበባዎቹንና ፡
ቀንዲሎቹን ፡ መኰስተሪያዎቹንም ፡ ከጥሩ ፡
፳፪ ወርቅ ፡ ሠራ ። ጕጠቶቹንም ፡ ድስቶቹንም ፡
ጭልፋዎቹንም ፡ ማንደጃዎቹንም ፡ ከጥሩ ፡
ወርቅ ፡ ሠራ ። የውስጠኛውም ፡ ቤት ፡ የቅድ
ስተ ፡ ቅዱሳን ፡ ደጆች ፡ የቤተ ፡ መቅደሱም ፡
ደጆች ፡ የወርቅ ፡ ነበሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ እንዲሁም ፡ ሰሎሞን ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ የሠራው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ተጨረሰ ። አባ
ቱም ፡ ዳዊት ፡ የቀደሰውን ፡ የብርና ፡ የወርቅ ፡
ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ሰሎሞን ፡ አምጥቶ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ በነበረው ፡ ግምጃ ፡ ቤት ፡
አኖረው ።

፪ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሰሎሞን ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ ከዳዊት ፡ ከተማ ፡
ከጽዮን ፡ ያወጡ ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤልን ፡ ሽማ
ግሌዎችና ፡ የነገድ ፡ አለቆችን ፡ ሁሉ ፡ የእስራ
ኤልንም ፡ ልጆች ፡ አባቶች ፡ ቤቶች ፡ መሳፍ
፫ ንት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሰበሰበ ። የእስራኤ
ልም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ በበ
፬ ዓሉ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ተከማቹ ። የእስራ
ኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሁሉ ፡ መጡ ÷ ሌዋው
፭ ያንም ፡ ታቦቱን ፡ አነሡ ። ታቦቱንም ፡ የመገና
ኛውንም ፡ ድንኳን ፡ በድንኳኑም ፡ ውስጥ ፡ የነ
በረውን ፡ የተቀደሰውን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ አመጡ ፤
እነዚህንም ፡ ሁሉ ፡ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑ ፡
፮ አመጡ ። ንጉሡም ፡ ሰሎሞን ፡ ከእርሱም ፡
ጋር ፡ የተሰበሰቡ ፡ የእስራኤል ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡
በታቦቱ ፡ ፊት ፡ ሆነው ፡ ከብዛት ፡ የተነሣ ፡ የማ
ይቈጠሩትንና ፡ የማይመጠኑትን ፡ በጎችና ፡ በሬ
፯ ዎች ፡ ይሠዉ ፡ ነበር ። ካህናቱም ፡ የእግዚአብ
ሔርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ታቦት ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ አም
ጥተው ፡ በቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፡ ውስጥ ፡ ከኪሩ
ቤል ፡ ክንፍ ፡ በታች ፡ በነበረው ፡ በስፍራው ፡
፰ አኖሩት ። ኪሩቤልም ፡ በታቦቱ ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡
ክንፎቻቸውን ፡ ዘርግተው ፡ ነበር ÷ ኪሩቤልም ፡
ታቦቱንና ፡ መሎጊያዎቹን ፡ በስተ ፡ ላዩ ፡ በኩል ፡
፱ ይሸፍኑ ፡ ነበር ። መሎጊያዎቹም ፡ ረጃጅሞች ፡
ነበሩና ፡ በቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፡ ፊት ፡ ከመቅ
ደሱ ፡ ውስጥ ፡ ጫፎቻቸው ፡ ይታዩ ፡ ነበር ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ከውጪ ፡ አይታዩም ፡ ነበር ፤ እስከ ፡
፲ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ እዚያ ፡ አሉ ። በታቦቱም ፡
ውስጥ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡
በወጡ ፡ ጊዜ ÷ እግዚአብሔርም ፡ ከእነርሱ ፡
ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ባደረገ ፡ ጊዜ ፡ ሙሴ ፡ በኮ
ሬብ ፡ ካስቀመጣቸው ፡ ከሁለቱ ፡ ጽላቶች ፡
በቀር ፡ ምንም ፡ አልነበረበትም ።

፲፩ በዚያም ፡ የነበሩት ፡ ካህናት ፡ ሁሉ ፡ ተቀድ
ሰው ፡ ነበር ÷ በሰሞናቸውም ፡ አልተከፈሉም ፡
፲፪ ነበር ፤ መዘምራንም ፡ የነበሩት ፡ ሌዋውያን ፡
ሁሉ ÷ አሳፍና ፡ ኤማን ፡ ኤዶታምም ፡ ልጆቻቸ
ውም ፡ ወንድሞቻቸውም ÷ ጥሩ ፡ በፍታ ፡ ለብ
ሰው ፡ ጸናጽልና ፡ በገና ፡ መሰንቆም ፡ እየመቱ ፡
በመሠዊያው ፡ አጠገብ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡
ቆመው ፡ ነበር ፤ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡
ካህናት ፡ መለከት ፡ ይነፉ ፡ ነበር ። ካህናቱም ፡
፲፫ ከመቅደሱ ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ÷ መለከቱንም ፡ የሚ
ነፉ ፡ መዘምራኑም ፡ በአንድነት ፡ ሆነው ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ እያመሰገኑና ፡ እያከበሩ ፡— እግ
ዚአብሔር ፡ ቸር ፡ ነውና ÷ ምሕረቱም ፡ ለዘላ
ለም ፡ ነውና ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡
እያሉ ፡ በአንድ ፡ ቃል ፡ ድምፃቸውን ፡ ወደ ፡
ላይ ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡ በመለከትና ፡ በጸናጽል ፡
በዜማም ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባመሰ
ገኑ ፡ ጊዜ ÷ ደመናው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡
፲፬ ሞላው ። የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ የእግዚ
አብሔርን ፡ ቤት ፡ ሞልቶት ፡ ነበርና ፡ ካህናቱ ፡
ከደመናው ፡ የተነሣ ፡ መቆምና ፡ ማገልገል ፡
አልተቻላቸውም ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ሰሎሞንም ፡— እግዚአብሔር ፡— በጨለማ ፡
፪ ውስጥ ፡ እኖራለሁ ፡ ብሎአል ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ለዘ
ላለም ፡ ትኖርበት ፡ ዘንድ ፡ ማደሪያ ፡ ቤትን ፡
፫ ሠራሁልህ ፡ አለ ። ንጉሡም ፡ ፊቱን ፡ ዘወር ፡
አድርጎ ፡ የእስራኤልን ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ መረቀ ፤
የእስራኤልም ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ ቆመው ፡ ነበር ።
፬ እርሱም ፡ አለ ፡— ለአባቴ ፡ ለዳዊት ፡ በአፉ ፡

የተናገረ ፡ በእጁም ፡ የፈጸመ ፡ የእስራኤል ፡
፭ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ፤ እርሱ ፦
ሕዝቤን ፡ ከግብጽ ፡ ካወጣሁበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡
ስሜ ፡ የሚጠራበት ፡ ቤት ፡ በዚያ ፡ ይሠራልኝ ፡
ዘንድ ፡ ከእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ ማንኛው
ንም ፡ ከተማ ፡ አልመረጥሁም ፤ በሕዝቤም ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ማን
፮ ፡ ንም ፡ አልመረጥሁም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ስሜ ፡
በዚያ ፡ እንዲጠራበት ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ መር
ጫለሁ ፥ በሕዝቤም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ እን
ዲሆን ፡ ዳዊትን ፡ መርጫለሁ ፡ ብሎአልና ።
፯ ፡ አባቴም ፡ ዳዊት ፡ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ በልቡ ፡
፰ ፡ አስቦ ፡ ነበር ። እግዚአብሔርም ፡ አባቴን ፡
ዳዊትን ፦ ለስሜ ፡ ቤት ፡ ትሠራ ፡ ዘንድ ፡
በልብህ ፡ አስበሃልና ፡ ይህን ፡ በልብህ ፡ መል
፱ ፡ ካም ፡ አደረግህ ። ነገር ፡ ግን ፡ ከወገብህ ፡ የሚ
ወጣው ፡ ልጅህ ፡ እርሱ ፡ ለስሜ ፡ ቤትን ፡ ይሠ
ራል ፡ እንጂ ፡ ቤት ፡ የምትሠራልኝ ፡ አንተ ፡
፲ ፡ አይደለህም ፡ አለው ። እግዚአብሔርም ፡ የተ
ናገረውን ፡ ቃል ፡ ፈጸመ ፤ እግዚአብሔርም ፡
ተስፋ ፡ እንደ ፡ ሰጠ ፡ በአባቴ ፡ በዳዊት ፡ ፋንታ ፡
ተነሣሁ ፥ በእስራኤልም ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ተቀ
መጥሁ ፥ ለእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአ
፲፩ ፡ ብሔር ፡ ስም ፡ ቤት ፡ ሠራሁ ። ከእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ ጋር ፡ ያደረገው ፡ የእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ ኪዳን ፡ ያለበትን ፡ ታቦት ፡ በዚያው ፡
ውስጥ ፡ አኖርሁ ።
፲፪ ፲፫ ሰሎሞንም ፡ ርዝመቱ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፥
ወርዱም ፡ አምስት ፡ ክንድ ፥ ቁመቱም ፡ ሦስት ፡
ክንድ ፡ የሆነ ፡ የናስ ፡ መደገፊያ ፡ ሠርቶ ፡ በአደ
ባባዩ ፡ መካከል ፡ ተክሎት ፡ ነበር ፥ በላዩም ፡
ቆመ ፥ በእስራኤልም ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡
በጕልበቱ ፡ ተንበርክኮ ፡ እጁን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡
ዘረጋ ፤ የእስራኤልም ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ እያዩ ፡
በእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ፊት ፡ ቆሞ ፡ እጆ
፲፬ ፡ ቹንም ፡ ዘርግቶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ አቤቱ ፡ የእ
ስራኤል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ በሰማይ ፡ ወይም ፡
በምድር ፡ አንተን ፡ የሚመስል ፡ አምላክ ፡
የለም ፤ በፍጹም ፡ ልባቸው ፡ በፊትህ ፡ ለሚ
ሄዱ ፡ ባሪያዎችህ ፡ ቃል ፡ ኪዳንንና ፡ምሕረትን ፡
፲፭ ፡ የምትጠብቅ ፥ ለባሪያህ ፡ ለአባቴ ፡ ለዳዊት ፡
የሰጠኸውን ፡ ተስፋ ፡ የጠበቅህ ፤ በአፍህ ፡ ተና
ገርህ ፥ ዛሬም ፡ እንደ ፡ ሆነው ፡ በእጅህ ፡ ፈጸም
፲፮ ፡ ኸው ። አሁንም ፥ አቤቱ ፡ የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ ሆይ ፦ አንተ ፡ በፊቴ ፡ እንደ ፡ ሄድህ ፡
ልጆችህ ፡ በሕጌ ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ መንገዳቸ
ውን ፡ ቢጠብቁ ፡ በእስራኤል ፡ ዙፋን ፡ የሚቀ
መጥ ፡ ሰው ፡ በፊቴ ፡ አታጣም ፡ ብለህ ፡ ተስፋ ፡
የሰጠኸውን ፡ ለባሪያህ ፡ ለአባቴ ፡ ለዳዊት ፡
፲፯ ፡ ጠብቅ ። አሁንም ፥ አቤቱ ፡ የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ ሆይ ፥ ለባሪያህ ፡ ለዳዊት ፡ የተናገርኸው ፡
ቃል ፡ ይጽና ።
፲፰ ፡ በውኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሰው ፡ ጋር ፡ በም
ድር ፡ ላይ ፡ ይኖራልን ? እነሆ ፥ ሰማይ ፡ ከሰማያ
ትም ፡ በላይ ፡ ያለ ፡ ሰማይ ፡ ይይዝህ ፡ ዘንድ ፡
አይችልም ፤ ይልቁንስ ፡ እኔ ፡ የሠራሁት ፡ ቤት ፡
፲፱ ፡ እንዴት ፡ ያንስ ፡ ይሆን ? ነገር ፡ ግን ፥ አቤቱ ፡
አምላኬ ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ ባሪያህ ፡ ጸሎትና ፡
ልመና ፡ ተመልከት ፥ ባሪያህም ፡ በፊትህ ፡ የሚ
፳ ፡ ጸልየውን ፡ ጸሎትና ፡ ጥሪውን ፡ ስማ ። ባሪያህ ፡
ወደዚህ ፡ ስፍራ ፡ የሚጸልየውን ፡ ጸሎት ፡
ትሰማ ፡ ዘንድ ፦ በዚያ ፡ ስሜ ፡ ይሆናል ፡ ወዳ
ልኸው ፡ ስፍራ ፥ ወደዚህ ፡ ቤት ፡ ዓይኖችህ ፡
፳፩ ፡ ቀንና ፡ ሌሊት ፡ የተገለጡ ፡ ይሁኑ ። ባሪያህና ፡
ሕዝብህ ፡ እስራኤል ፡ ወደዚህ ፡ ስፍራ ፡ የሚጸ
ልዩትን ፡ ልመና ፡ ስማ ፤ በማደሪያህ ፡ በሰማይ ፡
ስማ ፤ ሰምተህም ፡ ይቅር ፡ በል ።
፳፪ ፡ ሰው ፡ ባልንጀራውን ፡ ቢበድል ፥ በላዩም ፡
መሐላ ፡ ቢጫን ፥ እርሱም ፡ መጥቶ ፡ በዚህ ፡
፳፫ ፡ ቤት ፡ በመሠዊያህ ፡ ፊት ፡ ቢምል ፥ በሰማይ ፡
ስማ ፥ አድርግም ፥ በባሪያዎችህም ፡ ላይ ፡ ዳኛ ፡
ሁን ፥ በበደለኛውም ፡ ላይ ፡ ፍረድ ፥ መንገዱ
ንም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ መልስበት ፤ ንጹሑንም ፡
አጽድቀው ፥ እንደ ፡ ጽድቁም ፡ ክፈለው ።
፳፬ ፡ ሕዝብህም ፡ እስራኤል ፡ አንተን ፡ ስለ ፡ በደሉ ፡
በጠላት ፡ ፊት ፡ ድል ፡ ተመትተው ፡ ወደ ፡
አንተ ፡ ቢመለሱ ፥ ስምህንም ፡ ቢያከብሩ ፥ በዚ
ህም ፡ ቤት ፡ በፊትህ ፡ ቢጸልዩና ፡ ቢለምኑህ ፥
፳፭ ፡ አንተ ፡ በሰማይ ፡ ስማ ፥ የሕዝብህንም ፡ የእስ
ራኤልን ፡ ኃጢአት ፡ ይቅር ፡ በል ፤ ለእነርሱም ፡
ለአባቶቻቸውም ፡ ወደ ፡ ሰጥሃት ፡ ምድር ፡ መል
ሳቸው ።
፳፮ ፡ አንተን ፡ ስለ ፡ በደሉ ፡ ሰማያት ፡ በተዘጉ ፡
ጊዜ ፡ ዝናብም ፡ ባልዘነበ ፡ ጊዜ ፥ ወደዚህ ፡
ስፍራ ፡ ቢጸልዩ ፥ ስምህንም ፡ ቢያከብሩ ፥ ባስ
ጨነቅሃቸውም ፡ ጊዜ ፡ ከኃጢአታቸው ፡ ቢመ
፳፯ ፡ ለሱ ፥ አንተ ፡ በሰማይ ፡ ስማ ፥ የባሪያዎችህ
ንና ፡ የሕዝብህን ፡ የእስራኤልን ፡ ኃጢአት ፡
ይቅር ፡ በል ፥ የሚሄዱበትንም ፡ መልካም ፡
መንገድ ፡ አሳያቸው ፤ ለሕዝብህም ፡ ርስት ፡ አድ
ርገህ ፡ ለሰጠሃት ፡ ምድር ፡ ዝናብን ፡ ስጥ ።
፳፰ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ራብ ፡ ወይም ፡ ቸነፈር ፡
ወይም ፡ ዋግ ፡ ወይም ፡ አረማሞ ፡ ወይም ፡ አን
በጣ ፡ ወይም ፡ ኩብኩባ ፡ ቢሆን ፥ ጠላቶቻቸ
ውም ፡ የአገሩን ፡ ከተሞች ፡ ከብበው ፡ ቢያስ
ጨንቁአቸው ፥ ማናቸውም ፡ መቅሠፍትና ፡
፳፱ ፡ ደዌ ፡ ቢሆን ፥ ማንም ፡ ሰው ፡ ወይም ፡ ሕዝ
ብህ ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፥ ማናቸውም ፡ ሰው ፡
ሕመሙንና ፡ ኀዘኑን ፡ አውቆ ፡ ጸሎትና ፡ ልመና ፡
ቢያደርግ ፡ እጆቹንም ፡ ወደዚህ ፡ ቤት ፡ ቢዘ
፴ ፴፩ ፡ ረጋ ፥ ለአባቶቻችን ፡ በሰጠኸው ፡ ምድር ፡ ላይ ፡
በሚኖሩበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ይፈሩህ ፡ ዘንድ ፡
በመንገዶችህም ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፥ በማደሪያህ ፡
በሰማይ ፡ ስማ ፥ ይቅርም ፡ በል ፤ አንተ ፡ ብቻ ፡
የሰውን ፡ ልጆች ፡ ልብ ፡ ታውቃለህና ፡ ልቡን ፡
ለምታውቀው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ መንገዱ ፡
ሁሉ ፡ መጠን ፡ ክፈለው ።

፴፪ ከሕዝብህም ፡ ከእስራኤል ፡ ያልሆነ ፡ እንግዳ ፡ ስለ ፡ ታላቁ ፡ ስምህ ፡ ስለ ፡ ብርቱውም ፡ እጅህ ፡ ስለ ፡ ተዘረጋውም ፡ ክንድህ ፡ ከሩቅ ፡ አገር ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ÷ መጥቶም ፡ ወደዚህ ፡ ቤት ፡ በጸ ፴፫ ለየ ፡ ጊዜ ÷ አንተ ፡ በማደሪያህ ፡ በሰማይ ፡ ስማ ፤ የምድርም ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ስምህን ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ÷ እንደ ፡ ሕዝብህም ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ ይፈሩህ ፡ ዘንድ ÷ በዚህም ፡ በሠራሁት ፡ ቤት ፡ ስምህ ፡ እንደ ፡ ተጠራ ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ÷ እንግዳው ፡ የሚለምንህን ፡ ሁሉ ፡ አድርግ ።

፴፬ ሕዝብህም ፡ ጠላቶቻቸውን ፡ ለመውጋት ፡ አንተ ፡ በምትልካቸው ፡ መንገድ ፡ ቢወጡ ÷ አንተም ፡ ወደ ፡ መረጥሃት ፡ ወደዚህች ፡ ከተማ ፡ እኔም ፡ ለስምህ ፡ ወደ ፡ ሠራሁት ፡ ቤት ፡ ለአ ፴፭ ንተ ፡ ቢጸልዩ ÷ ጸሎታቸውንና ፡ ልመናቸውን ፡ በሰማይ ፡ ስማ ÷ ፍርድንም ፡ አድርግላቸው ።

፴፮ የማይበድል ፡ ሰው ፡ የለምና ፡ አንተን ፡ ቢበድሉ ÷ ተቈጥተሃም ፡ ለጠላት ፡ አሳልፈህ ፡ ብትሰጣቸው ÷ ሩቅም ፡ ወይም ፡ ቅርብ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ፴፯ አገር ፡ ቢማርኩአቸው ÷ በተማረኩበትም ፡ አገር ፡ ሆነው ፡ በልባቸው ፡ ንስሐ ፡ ቢገቡ ÷ በምርኮአቸውም ፡ አገር ፡ ሳሉ ፡ ተመልሰው ፡— ኃጢአት ፡ ሠርተናል ÷ በድለንማል ÷ ክፉም ፡ ፴፰ አድርገናል ፡ ብለው ፡ ቢለምኑህ ÷ በተማረኩበትም ፡ በምርኮአቸው ፡ አገር ፡ ሳሉ ፡ በፍጹም ፡ ልባቸውና ፡ በፍጹም ፡ ነፍሳቸው ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ቢመለሱ ÷ ለአባቶቻቸውም ፡ ወደ ፡ ሰጠሃት ፡ ወደ ፡ ምድራቸው ፡ ወደ ፡ መረጥሃትም ፡ ከተማ ፡ ለስምህም ፡ ወደ ፡ ሠራሁት ፡ ቤት ፡ ቢጸልዩ ÷ ፴፱ ጸሎታቸውንና ፡ ልመናቸውን ፡ በማደሪያህ ፡ በሰማይ ፡ ስማ ÷ ፍርድንም ፡ አድርግላቸው ፤ አንተንም ፡ የበደሉህን ፡ ሕዝብህን ፡ ይቅር ፡ በል ።

፵ አሁንም ÷ አምላኬ ፡ ሆይ ÷ በዚህ ፡ ስፍራ ፡ ወደሚሆነው ፡ ጸሎት ፡ ዓይኖችህ ፡ የተገለጡ ÷ ጆሮችህም ፡ የሚያደምጡ ፡ እንዲሆኑ ፡ እለም ፵፩ ንሃለሁ ። አሁንም ÷ አቤቱ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ ከኃይልህ ፡ ታቦት ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ዕረፍትህ ፡ ተነሣ ፤ አቤቱ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ ካህናትህ ፡ ደኅንነትን ፡ ይልበሱ ፤ ቅዱሳንህም ፡ በደስታ ፡ ደስ ፡ ይበላ ፵፪ ቸው ። አቤቱ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ የቀባኸውን ፡ ሰው ፡ ፊት ፡ አትመልስ ፡ ለባሪያህም ፡ ለዳዊት ፡ ያደረግህለትን ፡ ምሕረት ፡ አስብ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ሰሎሞንም ፡ ጸሎቱን ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ እሳት ፡ ከሰማይ ፡ ወርዶ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ ሌላ ፡ መሥዋዕቱን ፡ በላ ፤ የእግዚአብሔ ፪ ርም ፡ ክብር ፡ ቤቱን ፡ ሞላ ። የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ሞልቶት ፡ ነበርና ፡ ካህናቱ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፫ ቤት ፡ መግባት ፡ አልቻሉም ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ እሳቱ ፡ ሲወርድ ፡ የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ በቤቱ ፡ ላይ ፡ ሲሆን ፡ ያዩ ፡ ነበር ፤ በወለሉም ፡ ላይ ፡ በግምባራቸው ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ተደፍተው ፡ ሰገዱ ፡— እርሱ ፡ መልካም ፡ ነውና ÷ ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፡ ብለውም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰገኑ ።

፬ ንጉሡም ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርቡ ፡ ነበር ። ፭ ንጉሡም ፡ ሰሎሞን ፡ ሀያ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ በሬዎችና ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሺህ ፡ በጎች ፡ ሠዋ ። እንዲሁ ፡ ንጉሡና ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ቀደሱ ። ፮ ካህናቱም ፡ በየሥርዓታቸው ÷ ሌዋውያኑም ፡ ደግሞ ፡— ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ የሚለውን ፡ የዳዊትን ፡ መዝሙር ፡ እየዘመሩ ÷ ንጉሡ ፡ ዳዊት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለማመስገን ፡ የሠራውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የዜማ ፡ ዕቃ ፡ ይዘው ፡ ቆመው ፡ ነበር ፤ ካህናቱም ፡ በፊታቸው ፡ መለከት ፡ ይነፉ ፡ ነበር ፤ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ቆመው ፡ ነበር ። ፯ ሰሎሞን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ፊት ፡ የነበረውን ፡ የአደባባዩን ፡ ውስጥ ፡ ቀደሰ ፤ ሰሎሞንም ፡ የሠራው ፡ የናስ ፡ መሠዊያ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የእህሉን ፡ ቍርባን ፡ ስቡንም ፡ መያዝ ፡ አልቻለምና ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የደኅንነቱን ፡ መሥዋዕት ፡ ስብ ፡ በዚያ ፡ አቀረበ ።

፰ ሰሎሞንም ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ጉባኤ ፡ የሆኑ ÷ ከሐማት ፡ መግቢያ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ግብጽ ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ፡ ያሉ ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ÷ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ አደ ፱ ረጉ ። ሰባት ፡ ቀንም ፡ መሠዊያውን ፡ ቀድሰው ÷ ሰባት ፡ ቀንም ፡ በዓል ፡ አድርገው ፡ ነበርና ፡ በስምንተኛው ፡ ቀን ፡ የተቀደሰውን ፡ ጉባኤ ፡ ፲ አደረጉ ። በሰባተኛውም ፡ ወር ፡ በሀያ ፡ ሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ሕዝቡን ፡ ወደ ፡ ድንኳናቸው ፡ አሰናበተ ፤ እግዚአብሔር ፡ ለዳዊትና ፡ ለሰሎሞን ፡ ለሕዝቡም ፡ ለእስራኤል ፡ ስላደረገው ፡ ቸርነት ፡ ደስ ፡ ብሎአቸው ፡ ሐሤትን ፡ እያደረጉ ፡ ሄዱ ።

፲፩ ሰሎሞንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤትና ፡ የንጉሡን ፡ ቤት ፡ ጨረሰ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ቤትና ፡ በራሱ ፡ ቤት ፡ ይሠራው ፡ ዘንድ ፡ በልቡ ፡ ያሰበውን ፡ ሁሉ ፡ አከናወነ ። ፲፪ እግዚአብሔርም ፡ ለሰሎሞን ፡ በሌሊት ፡ ተገለጠ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— ጸሎትህን ፡ ሰምቻለሁ ÷ ይህንም ፡ ስፍራ ፡ ለራሴ ፡ ለመሥዋዕት ፡ ቤት ፡ መርጫ ፲፫ ለሁ ። ዝናብ ፡ እንዳይወርድ ፡ ሰማያቱን ፡ ብዘጋ ÷ ወይም ፡ ምድሪቱን ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ አንበጣን ፡ በዝዘው ÷ ወይም ፡ በሕዝብ ፡ ላይ ፡ ቸነፈር ፡ ፲፬ ብሰድድ ÷ በስሜ ፡ የተጠሩት ፡ ሕዝቤ ፡ ሰውነታቸውን ፡ አዋርደው ፡ ቢጸልዩ ÷ ፊቴንም ፡ ቢፈልጉ ÷ ከክፉ ፡ መንገዳቸውም ፡ ቢመለሱ ÷ በሰማይ ፡ ሆኜ ፡ እሰማለሁ ÷ ኃጢአታቸውንም ፡ ይቅር ፡ እላለሁ ÷ ምድራቸውንም ፡ እፈውሳ ፲፭ ለሁ ። አሁንም ፡ በዚህ ፡ ስፍራ ፡ ለሚጸለይ ፡ ጸሎት ፡ ዓይኖቼ ፡ ይገለጣሉ ÷ ጆሮቼም ፡ ያደም

፲፮፤ ጣሉ ። አሁንም ፡ ስሜ ፡ ለዘላለም ፡ በዚያ ፡
ይኖር ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡ ቤት ፡ መርጫለሁ ፡ ቀድ
ሻለሁም ፤ ዓይኖቼና ፡ ልቤም ፡ ዘወትር ፡ በዚያ ፡
፲፯፤ ይሆናሉ ። አንተም ፡ ደግሞ ፡ አባትህ ፡ ዳዊት ፡
እንደ ፡ ሄደ ፡ በፊቴ ፡ ብትሄድ ፥ እንዳዘዝሁ
ህም ፡ ሁሉ ፡ ብታደርግ ፥ ሥርዓቴንና ፡ ፍርዴ
፲፰፤ ንም ፡ ብትጠብቅ ፥ ከአባትህ ፡ ከዳዊት ፡ ጋር ፡—
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ የሚሆን ፡ ከዘርህ ፡
አይታጣም ፡ ብዬ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ እንዳደረግሁ ፡
የመንግሥትህን ፡ ዙፋን ፡ አጸናለሁ ።

፲፱፤ እናንተ ፡ ግን ፡ እኔን ፡ ከመከተል ፡ ብትመ
ለሱ ፥ የሰጠኋችሁንም ፡ ሥርዓቴንና ፡ ትእዛዜን ፡
ብትተዉ ፥ ሄዳችሁም ፡ ሌሎችን ፡ አማልክት ፡
፳፤ ብታመልኩ ፡ ብትሰግዱላቸውም ፥ ለአባቶቻ
ችሁ ፡ ከሰጠኋቸው ፡ ምድር ፡ እነቅላችኋለሁ ፤
ለስሜም ፡ የቀደስሁትን ፡ ይህን ፡ ቤት ፡ ከፊቴ ፡
እጥለዋለሁ ፥ በአሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡
፳፩፤ ምሳሌና ፡ ተረት ፡ አደርገዋለሁ ። ከፍ ፡ ከፍ ፡
ብሎ ፡ የነበረውንም ፡ ይህን ፡ ቤት ፡ እያዩ ፡ በዚያ ፡
የሚያልፉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡— እግዚአብሔር ፡
በዚህ ፡ አገርና ፡ በዚህ ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እን
፳፪፤ ዲህ ፡ አደረገ ? ብለው ፡ ይደነቃሉ ። መልሰ
ውም ፡— ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ያወጣቸውን ፡ የአባ
ቶቻቸውን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትተው ፡
ሌሎችን ፡ አማልክት ፡ ስለ ፡ ተከተሉ ፥ ስለ ፡ ሰገ
ዱላቸውም ፥ ስለ ፡ አመለኩአቸውም ፥ ስለዚህ ፡
ይህን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አመጣባቸው ፡
ይላሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ሰሎሞን ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ቤትና ፡ የራሱን ፡ ቤት ፡ የሠራበት ፡ ሀያ ፡
፪፤ ዓመት ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፥ ኪራም ፡ ለሰሎሞን ፡
የሰጠውን ፡ ከተሞች ፡ ሰሎሞን ፡ ሠራቸው ፥
የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ አኖረባቸው ።
፫፤ ሰሎሞንም ፡ ወደ ፡ ሐማትሱባ ፡ ሄደ ፡ አሸ
፬፤ ነፋትም ። በምድረ ፡ በዳም ፡ ያለውን ፡ ተድ
ሞርን ፥ በሐማትም ፡ የሠራቸውን ፡ የዕቃ ፡
፭፤ ቤቱን ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ሠራ ። ደግሞም ፡
ቅጥርና ፡ መዝጊያ ፡ መወርወሪያም ፡ የነበራቸ
ውን ፡ የተመሸጉትን ፡ ከተሞች ፡ ላይኛውን ፡
ቤትሖሮን ፡ ታችኛውንም ፡ ቤትሖሮን ፡ ሠራ ።
፮፤ ባዕላትንም ፥ ለሰሎሞንም ፡ የነበሩትን ፡ የዕቃ ፡
ቤት ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፥ የሰረገላውንም ፡ ከተ
ሞች ፡ ሁሉ ፥ የፈረሰኞችንም ፡ ከተሞች ፥ በኢ
የሩሳሌምም ፡ በሊባኖስም ፡ በመንግሥቱም ፡
ምድር ፡ ሁሉ ፡ ሰሎሞን ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ የወ
ደደውን ፡ ሁሉ ፡ ሠራ ።
፯፤ ከኬጢያውያንም ፡ ከአሞራውያንም ፡ ከፌ
ርዜያውያንም ፡ ከኤዊያውያንም ፡ ከኢያቡሳው
ያንም ፡ የቀሩትን ፡ ከእስራኤል ፡ ወገን ፡ ያልሆ
፰፤ ኑትን ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፥ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
ያላጠፉአቸውን ፥ በኋላቸው ፡ በምድር ፡ ላይ ፡
የቀሩትን ፡ ልጆቻቸውን ፡ ሰሎሞን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡
ድረስ ፡ ገባሮች ፡ አድርጎ ፡ መለመላቸው ። ሰሎ
፱፤ ሞንም ፡ ለሥራው ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ማን
ንም ፡ ባሪያ ፡ አላደረገም ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ ሰልፈ
ኞች ፥ የሹማምቶችም ፡ አለቆች ፥ የሰረገሎ
፲፤ ችና ፡ የፈረሰኞች ፡ ባልደራሶች ፡ ነበሩ ። እነ
ዚህም ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ሠልጥነው ፡ የነበሩ ፡
የንጉሡ ፡ የሰሎሞን ፡ ዓይነተኞች ፡ አለቆች ፡
ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ነበሩ ።

፲፩፤ ሰሎሞንም ፡— የእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ የገ
ባበት ፡ ስፍራ ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ፡ ሚስቴ ፡ በእስ
ራኤል ፡ ንጉሥ ፡ በዳዊት ፡ ቤት ፡ አትቀመጥም ፡
ሲል ፡ የፈርዖንን ፡ ልጅ ፡ ከዳዊት ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡
ሠራላት ፡ ቤት ፡ አወጣት ።

፲፪፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሰሎሞን ፡ በወለሉ ፡ ፊት ፡
በሠራው ፡ በእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡
፲፫፤ አቀረበ ። ሙሴም ፡ እንዳዘዘ ፡ እንደ ፡ ሥርዓታ
ቸው ፡ በየቀኑ ፡ ሁሉ ፥ በየሰንበታቱም ፥ በየመ
ባቻዎቹም ፥ በየተወሰኑትም ፡ በዓላት ፥ በየዓ
መቱ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ በየቂጣው ፡ በዓልና ፡ በየ
ሰባቱ ፡ ሱባዔ ፡ በዓል ፡ በየዳሱም ፡ በዓል ፡ ቍር
ባን ፡ ያቀርቡ ፡ ነበር ።

፲፬፤ የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ ዳዊት ፡ እንዲህ ፡
አዝዞ ፡ ነበርና ፡ ካህናቱን ፡ እንደ ፡ አባቱ ፡ እንደ ፡
ዳዊት ፡ ሥርዓት ፡ በየአገልግሎታቸው ፡ ሰሞን ፡
ከፈላቸው ፤ ሌዋውያንም ፡ እንደ ፡ ሥርዓታ
ቸው ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ፥ በካህናቱም ፡ ፊት ፡
ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡ በየሰሞናቸው ፡ ከፈላቸው ፤
በረኞቹንም ፡ ደግሞ ፡ በየበሩ ፡ ሁሉ ፡ በየሰሞና
፲፭፤ ቸው ፡ ከፈላቸው ። እነርሱም ፡ ንጉሡ ፡ ስለ ፡
ነገሩ ፡ ሁሉና ፡ ስለ ፡ መዝገቡ ፡ ካህናቱንና ፡ ሌዋ
ውያኑን ፡ ያዘዘውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አልተላለፉም ።
፲፮፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ መሠረት ፡ ከተጣለ ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ተጨረሰ ፡ ድረስ ፡ የሰሎሞን ፡
ሥራ ፡ ሁሉ ፡ የተዘጋጀ ፡ ነበረ ። የእግዚአብ
ሔርም ፡ ቤት ፡ ተፈጸመ ።

፲፯፤ ሰሎሞንም ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ በኤዶምያስ ፡
ምድር ፡ በባሕር ፡ ዳር ፡ ወዳሉ ፡ ወደ ፡ ዔጽዮን
፲፰፤ ጋብርና ፡ ወደ ፡ ኤሎት ፡ ሄደ ። ኪራምም ፡
መርከቦችንና ፡ የባሕርን ፡ ነገር ፡ የሚያውቁ
ትን ፡ መርከበኞች ፡ በባሪያዎቹ ፡ እጅ ፡ ሰደደ
ለት ፤ እነርሱም ፡ ከሰሎሞን ፡ ባሪያዎች ፡ ጋር ፡
ወደ ፡ አፌር ፡ መጡ ፥ ከዚያም ፡ አራት ፡ መቶ ፡
አምሳ ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፡ ወስደው ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ሰሎሞን ፡ አመጡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩፤ የሳባም ፡ ንግሥት ፡ የሰሎሞንን ፡ ዝና ፡ በሰ
ማች ፡ ጊዜ ፡ በግመሎች ፡ ላይ ፡ ሽቱና ፡ ብዙ ፡
ወርቅ ፡ የከበረም ፡ ዕንቍ ፡ አስጭና ፡ ከታላቅ ፡
ጓዝ ፡ ጋር ፡ ሰሎሞንን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በእንቆቅ
ልሽ ፡ ትፈትነው ፡ ዘንድ ፡ መጣች ፤ ወደ ፡ ሰሎ
ሞንም ፡ በገባች ፡ ጊዜ ፡ በልብዋ ፡ ያለውን ፡
፪፤ ሁሉ ፡ አጫወተችው ። ሰሎሞንም ፡ የጠየቀች

ውን ፡ ሁሉ ፡ ፈታላት ፤ ሰሎሞንም ፡ ያልፈ
ታው ፡ ስውር ፡ ነገር ፡ አልነበረም ። ፫ የሳባም ፡
ንግሥት ፡ የሰሎሞንን ፡ ጥበብ ፥ ሠርቶትም ፡
፬ የነበረውን ፡ ቤት ፥ የማዕዱንም ፡ መብል ፥ የብ
ላቴኖቹንም ፡ አቀማመጥ ፥ የሎሌዎቹንም ፡ አሠ
ራር ፡ አለባበሳቸውንም ፥ ጠጅ ፡ አሳላፊዎቹ
ንም ፡ አለባበሳቸውንም ፥ በእግዚአብሔርም ፡
ቤት ፡ የሚያሳርገውን ፡ መሥዋዕት ፡ በየች ፡
ጊዜ ፡ መንፈስ ፡ አልቀረላትም ። ፭ ንጉሡንም፡
አለችው ፡— ስለ ፡ ነገርህና ፡ ስለ ፡ ጥበብህ ፡ በአ
ገሬ ፡ ሳለሁ ፡ የሰማሁት ፡ ዝና ፡ እውነት ፡ ነው ።
፮ እኔ ፡ ግን ፡ መጥቼ ፡ በዓይኔ ፡ እስካየሁ ፡ ድረስ ፡
የነገሩኝን ፡ አላመንሁም ፤ እነሆ ፥ የጥበብህን ፡
ታላቅነት ፡ እኩሌታ ፡ አልነገሩኝም ፤ ከሰማሁት ፡
ዝና ፡ ትበልጣለህ ። ፯ በፊትህ ፡ ሁልጊዜ ፡ የሚ
ቆሙ ፡ ጥበብህንም ፡ የሚሰሙ ፡ ሰዎችህና ፡ እነ
ዚህ ፡ ባሪያዎችህ ፡ ምስጉኖች ፡ ናቸው ። ፰ በአ
ምላክህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ንጉሥ ፡ እን
ድትሆን ፡ በዙፋኑ ፡ ላይ ፡ ያስቀምጥህ ፡ ዘንድ ፡
የወደደህ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ብሩክ ፡
ይሁን ፤ አምላክህ ፡ እስራኤልን ፡ ለዘላለም ፡
ያጸናቸው ፡ ዘንድ ፡ ወድዶአቸዋልና ፡ ስለዚህ ፡
ፍርድና ፡ ጽድቅ ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ በላያቸው ፡
አነገሠህ ።

፱ ለንጉሡም ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፥
እጅግም ፡ ብዙ ፡ ሽቱ ፥ የከበረም ፡ ዕንቍ ፡ ሰጠ
ችው ፤ የሳባም ፡ ንግሥት ፡ ለንጉሡ ፡ ለሰሎ
ሞን ፡ እንደ ፡ ሰጠችው ፡ ያለ ፡ ሽቱ ፡ ከቶ ፡ አል
ነበረም ። ፲ ከኦፊርም ፡ ወርቅ ፡ ያመጡ ፡ የኪ
ራም ፡ ባሪያዎችና ፡ የሰሎሞን ፡ ባሪያዎች ፡ የሰ
ንደል ፡ እንጨትና ፡ የከበረ ፡ ዕንቍ ፡ ደግሞ ፡
አመጡ ። ፲፩ ንጉሡም ፡ ከሰንደሉ ፡ እንጨት ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ ቤትና ፡ ለንጉሡ ፡ ቤት ፡ ደርብ ፥
ለመዘምራኑም ፡ መሰንቆና ፡ በገና ፡ አደረገ ፤
እንደዚህም ፡ ያለ ፡ በይሁዳ ፡ ምድር ፡ ከቶ ፡ አል
ታየም ፡ ነበር ። ፲፪ የሳባም ፡ ንግሥት ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ ከመጣችው ፡ የሚበልጥ ፥ ንጉሡ ፡ ሰሎ
ሞን ፡ የወደደችውን ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱም ፡ የለ
መነችውን ፡ ሁሉ ፡ ሰጣት ፤ እርስዋም ፡ ተመልሳ ፡
ከባሪያዎችዋ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ምድርዋ ፡ ሄደች ።

፲፫ ነጋድራሶችና ፡ ነጋዴዎች ፡ ካመጡለት ፡ ሌላ ፡
በየዓመቱ ፡ ወደ ፡ ሰሎሞን ፡ የሚመጣ ፡ የወርቅ ፡
ሚዛን ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ ስድስት ፡ መክ
ሊት ፡ ወርቅ ፡ ነበረ ። ፲፬ የዓረብም ፡ ነገሥታት ፡
ሁሉ ፡ የምድሩም ፡ ሹማምት ፡ ወርቅና ፡ ብር ፡
ወደ ፡ ሰሎሞን ፡ ያመጡ ፡ ነበር ። ፲፭ ንጉሡም ፡
ሰሎሞን ፡ በጥፍጥፍ ፡ ወርቅ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡
አላባሽ ፡ አግሬ ፡ ጋሻ ፡ አሠራ ፤ በአንዱም ፡ አላ
ባሽ ፡ አግሬ ፡ ጋሻ ፡ ውስጥ ፡ የገባው ፡ ጥፍጥፍ ፡
ወርቅ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ሰቅል ፡ ነበረ ። ፲፮ ከጥፍ
ጥፍም ፡ ወርቅ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ጋሻ ፡ አሠራ ፤
በአንዱም ፡ ጋሻ ፡ የገባው ፡ ወርቅ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡
ሰቅል ፡ ነበረ ፤ ንጉሡም ፡ የሊባኖስ ፡ ዱር ፡ በተ
ባለው ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ አኖራቸው ። ፲፯ ንጉሡም ፡
ደግሞ ፡ ከዝሆን ፡ ጥርስ ፡ ታላቅ ፡ ዙፋን ፡ አሠራ ፥
በጥሩ ፡ ወርቅም ፡ ለበጠው ። ፲፰ ከዙፋኑም ፡ ጋር ፡
ተጋጥመው ፡ ወደ ፡ ዙፋኑም ፡ የሚያስኬዱ ፡
ስድስት ፡ እርከኖች ፡ ነበሩ ፤ የወርቅ ፡ ብርኩ
ማም ፡ ነበረ ፤ በዚህና ፡ በዚያም ፡ በመቀመጫው ፡
አጠገብ ፡ ሁለት ፡ የክንድ ፡ መደገፊያዎች ፡ ነበ
ሩበት ፥ በመደገፊያዎችም ፡ አጠገብ ፡ ሁለት ፡
አንበሶች ፡ ቆመው ፡ ነበር ። ፲፱ በስድስቱም ፡ እር
ከኖች ፡ ላይ ፡ በዚህና ፡ በዚያ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡
አንበሶች ፡ ቆመው ፡ ነበር ፤ በመንግሥታት ፡
ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡ አልተሠራም ።
፳ ንጉሡም ፡ ሰሎሞን ፡ የሚጠጣበት ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡
የወርቅ ፡ ነበረ ፥ የሊባኖስ ፡ ዱር ፡ በተባለውም ፡
ቤቱ ፡ የነበረው ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ጥሩ ፡ ወርቅ ፡
ነበረ ፤ በሰሎሞን ፡ ዘመን ፡ ብር ፡ ከቶ ፡ አይቈ
ጠርም ፡ ነበር ። ፳፩ ለንጉሡም ፡ ከኪራም ፡ ባሪያ
ዎች ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ተርሴስ ፡ የሚሄዱ ፡ መርከ
ቦች ፡ ነበሩት ፤ በሦስት ፡ በሦስት ፡ ዓመትም ፡
አንድ ፡ ጊዜ ፡ የተርሴስ ፡ መርከቦች ፡ ወርቅና ፡
ብር ፡ የዝሆንም ፡ ጥርስ ፡ ዝንጀሮና ፡ ዝኆርጕር ፡
ወፍም ፡ ይዘው ፡ ይመጡ ፡ ነበር ።

፳፪ ንጉሡም ፡ ሰሎሞን ፡ ከምድር ፡ ነገሥታት ፡
ሁሉ ፡ በባለጠግነትና ፡ በጥበብ ፡ በለጠ ። ፳፫ የም
ድርም ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡
በልቡ ፡ ያኖረውን ፡ ጥበቡን ፡ ይሰሙ ፡ ዘንድ ፡
የሰሎሞንን ፡ ፊት ፡ ሊያዩ ፡ ይመኙ ፡ ነበር ።
፳፬ እያንዳንዱም ፡ ገጸ ፡ በረከቱን ፥ የወርቅንና ፡
የብርን ፡ ዕቃ ፥ ልብስንና ፡ የጦር ፡ መሣሪያን ፥
ሽቱውንም ፥ ፈረሶችንና ፡ በቅሎችን ፡ እየያዘ ፡
በየዓመቱ ፡ ያመጣ ፡ ነበር ። ፳፭ ሰሎሞንም ፡ ለፈረ
ሶችና ፡ ለሰረገሎች ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ጋጥ ፥
አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህም ፡ ፈረሰኞች ፡ ነበሩት ፥
በሰረገሎችም ፡ ከተሞች ፥ ከንጉሡም ፡ ጋር ፡
በኢየሩሳሌም ፡ አኖራቸው ። ፳፮ ከኤፍራጥስም ፡
ወንዝ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ፍልስጥኤም ፡ ምድርና ፡
እስከ ፡ ግብጽ ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ባሉ ፡ ነገሥታት ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነገሠ ። ፳፯ ንጉሡም ፡ ብሩን ፡ በኢየ
ሩሳሌም ፡ እንደ ፡ ድንጋይ ፡ እንዲበዛ ፡ አደረ
ገው ፤ የዝግባውንም ፡ እንጨት ፡ ብዛት ፡ በቈላ ፡
እንደሚበቅል ፡ ሾላ ፡ አደረገው ። ፳፰ ለሰሎሞንም ፡
ፈረሶች ፡ ከግብጽና ፡ ከየአገሩ ፡ ሁሉ ፡ ያመጡ
ለት ፡ ነበር ።

፳፱ የቀረውም ፡ ፊተኛውና ፡ ኋለኛው ፡ የሰሎ
ሞን ፡ ነገር ፡ በነቢዩ ፡ በናታን ፡ ታሪክ ፥ በሴ
ሎናዊውም ፡ በአሒያ ፡ ትንቢት ፥ ስለ ፡ ናባ
ጥም ፡ ልጅ ፡ ስለ ፡ ኢዮርብዓም ፡ ባየው ፡ በባለ
ራእዩ ፡ በአዶ ፡ ራእይ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ?
፴ ሰሎሞንም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። ፴፩ ሰሎሞንም ፡ ከአ
ባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በአባቱም ፡ በዳዊት ፡
ከተማ ፡ ተቀበረ ፤ ልጁም ፡ ሮብዓም ፡ በእርሱ ፡
ፋንታ ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ያነግሡት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ሴኬም ፡ መጥተው ፡ ነበርና ፡ ሮብዓም ፡ ወደ ፡ ፪ ሴኬም ፡ ሄደ ። የናባጥ ፡ ልጅ ፡ ኢዮርብዓምም ፡ ከንጉሡ ፡ ከሰሎሞን ፡ ፊት ፡ ሸሽቶ ፡ በግብጽ ፡ ይኖር ፡ ነበርና ፡ ይህን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ኢዮርብ ፫ ዓም ፡ ከግብጽ ፡ ተመለሰ ። ልከውም ፡ ጠሩት ፤ ኢዮርብዓምና ፡ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ መጥተው ፡ ፬ ሮብዓምን ፡— አባትህ ፡ ቀንበር ፡ አክብዶብን ፡ ነበር ፤ አሁንም ፡ አንተ ፡ ጽኑውን ፡ የአባትህን ፡ አገዛዝ ፥ በላያችንም ፡ የጫነውን ፡ የከበደውን ፡ ቀንበር ፡ አቅልልልን ፥ እኛም ፡ እንገዛልሃለን ፡ ፭ ብለው ፡ ተናገሩት ። እርሱም ፡— ከሦስት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ተመለሱ ፡ አላቸው ። ሕዝቡም ፡ ሄዱ ።

፮ ንጉሡም ፡ ሮብዓም ፡— ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ እመልስለት ፡ ዘንድ ፡ የምትመክሩኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብሎ ፡ አባቱ ፡ ሰሎሞን ፡ በሕይወት ፡ ሳለ ፡ በፊቱ ፡ ይቆሙ ፡ ከነበሩት ፡ ሽማግሌዎች ፡ ፯ ጋር ፡ ተማከረ ። እነርሱም ፡— ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ቸርነት ፡ ብታደርግላቸው ፥ ደስም ፡ ብታሰኛቸው ፥ በገርነትም ፡ ብትናገራቸው ፥ ለዘላለም ፡ ባሪያዎች ፡ ይሆኑልሃል ፡ ብለው ፡ ተናገሩት ። ፰ እርሱ ፡ ግን ፡ ሽማግሌዎች ፡ የመከሩትን ፡ ነገር ፡ ትቶ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ካደጉትና ፡ በፊቱ ፡ ይቆሙ ፡ ፱ ከነበሩት ፡ ብላቴኖች ፡ ጋር ፡ ተማከረ ። እርሱም ፡— አባትህ ፡ የጫነብንን ፡ ቀንበር ፡ አቅልልልን ፡ ለሚሉኝ ፡ ሕዝብ ፡ እመልስላቸው ፡ ዘንድ ፡ የምትመክሩኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አላ ፲ ቸው ። ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ያደጉት ፡ ብላቴኖች ፡— አባትህ ፡ ቀንበር ፡ አክብዶብን ፡ ነበር ፥ አንተ ፡ ግን ፡ አቅልልልን ፡ ለሚሉህ ፡ ሕዝብ ፡— ታናሽቱ ፡ ጣቴ ፡ ከአባቴ ፡ ወገብ ፡ ትወፍራለች ፤ ፲፩ አሁንም ፡ አባቴ ፡ ከባድ ፡ ቀንበር ፡ ጭኖባችሁ ፡ ነበር ፥ እኔ ፡ ግን ፡ በቀንበራችሁ ፡ ላይ ፡ እጨምራለሁ ፤ አባቴ ፡ በአለንጋ ፡ ገርፎአችሁ ፡ ነበር ፥ እኔ ፡ ግን ፡ በጊንጥ ፡ እገርፋችኋለሁ ፡ በላቸው ፡ ብለው ፡ ተናገሩት ።

፲፪ ንጉሡም ፡— በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ተመለሱ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ኢዮርብዓምና ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ፲፫ ሮብዓም ፡ መጡ ። ንጉሡም ፡ ጽኑ ፡ ምላሽ ፡ መለሰላቸው ፤ ንጉሡም ፡ ሮብዓም ፡ የሽማግሌ ፲፬ ዎቹን ፡ ምክር ፡ ትቶ ፡— አባቴ ፡ ቀንበር ፡ አክብዶባችሁ ፡ ነበር ፥ እኔ ፡ ግን ፡ እጨምርበታለሁ ፤ አባቴ ፡ በአለንጋ ፡ ገርፎአችሁ ፡ ነበር ፥ እኔ ፡ ግን ፡ በጊንጥ ፡ እገርፋችኋለሁ ፡ ብሎ ፡ ፲፭ እንደ ፡ ብላቴኖቹ ፡ ምክር ፡ ተናገራቸው ። እግዚአብሔርም ፡ በሴሎናዊው ፡ በአሒያ ፡ አድርጎ ፡ ለናባጥ ፡ ልጅ ፡ ለኢዮርብዓም ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ እንዲያጸና ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ተወስኖ ፡ ነበርና ፡ ንጉሡ ፡ ሕዝቡን ፡ አልሰማም ።

፲፮ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ንጉሡ ፡ እንዳልሰማቸው ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡ ፡— በዳዊት ፡ ዘንድ ፡ ምን ፡ ክፍል ፡ አለን ? በእሴይም ፡ ልጅ ፡ ዘንድ ፡ ርስት ፡ የለንም ፤ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ እየድንኳኖቻችሁ ፡ ተመለሱ ፤ ዳዊት ፡ ሆይ ፥ አሁን ፡ ቤትህን ፡ ተመልከት ፡ ብለው ፡ ለንጉሡ ፡ መለሱለት ። እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እየድንኳኖ ፲፯ ቻቸው ፡ ሄዱ ። በይሁዳ ፡ ከተሞች ፡ በተቀመጡት ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ግን ፡ ሮብ ፲፰ ዓም ፡ ነገሠባቸው ። ንጉሡም ፡ ሮብዓም ፡ አስገባሪውን ፡ አዶራምን ፡ ሰደደ ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በድንጋይ ፡ ወገሩት ፥ ሞተም ፤ ንጉሡም ፡ ሮብዓም ፡ ፈጥኖ ፡ ወደ ፡ ሰረገላው ፡ ፲፱ ወጣ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ሸሸ ። እስራኤልም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ከዳዊት ፡ ቤት ፡ ሸፈተ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ሮብዓምም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ እስራኤልን ፡ ወግተው ፡ መንግሥቱን ፡ ወደ ፡ ሮብዓም ፡ ይመልሱ ፡ ዘንድ ፡ ከይሁዳና ፡ ከብንያም ፡ ቤት ፡ የተመረጡትን ፡ አንድ ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ ሺህ ፡ ሰልፈኞች ፡ ሰዎች ፡ ሰበሰበ ። ፪ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ሸማያ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ፫ ለይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ለሰሎሞን ፡ ልጅ ፡ ለሮብዓም ፥ በይሁዳና ፡ በብንያምም ፡ ላሉት ፡ ለእስራኤል ፡ ፬ ሁሉ ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ይህ ፡ ነገር ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ነውና ፡ አትውጡ ፥ ወንድሞቻችሁንም ፡ አትውጉ ፤ እያንዳንዱም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ይመለስ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ። የእግዚአብሔርንም ፡ ቃል ፡ ሰሙ ፥ በኢዮርብዓምም ፡ ላይ ፡ ከመሄድ ፡ ተመለሱ ።

፭ ሮብዓምም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተቀመጠ ፥ በይ ፮ ሁዳም ፡ የተመሸጉትን ፡ ከተሞች ፡ ሠራ ። በይሁዳና ፡ በብንያም ፡ ያሉትንም ፡ የተመሸጉትን ፡ ከተሞች ፥ ቤተ ፡ ልሔምን ፥ ኤጣምን ፥ ቴቁ ፯፡፰ ሔን ፥ ቤትጹርን ፥ ሦኮን ፥ ዓዶላምን ፥ ጌትን ፥ ፱ መሪሳን ፥ ዚፍን ፥ አዶራይምን ፥ ለኪሶን ፥ ዓዜ ፲ ቃን ፥ ጾርዓን ፥ ኤሎንን ፥ ኬብሮንን ፡ ሠራ ። ፲፩ ምሽጎቹንም ፡ አጠነከረ ፥ አለቆችንም ፡ አኖረባቸው ፥ ምግቡንም ፡ ዘይቱንም ፡ የወይን ፡ ጠጁ ፲፪ ንም ፡ አከማቸባቸው ። በከተሞቹ ፡ ሁሉ ፡ ጋሻና ፡ ጦርን ፡ አኖረ ፥ ከተሞቹንም ፡ እጅግ ፡ አጠነከራቸው ፤ ይሁዳና ፡ ብንያምም ፡ የእርሱ ፡ ወገን ፡ ነበሩ ።

፲፫ በእስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ የነበሩ ፡ ካህናትና ፡ ሌዋውያን ፡ ከየአገራቸው ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ፲፬ እርሱ ፡ መጡ ። የእግዚአብሔርም ፡ ካህናት ፡ እንዳይሆኑ ፡ ኢዮርብዓምና ፡ ልጆቹ ፡ አስለቀቀዋቸው ፡ ነበርና ፡ ሌዋውያን ፡ መሰምርያቸውንና ፡ ቦታቸውን ፡ ትተው ፡ ወደ ፡ ይሁዳና ፡ ፲፭ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጡ ። እርሱ ፡ ግን ፡ ለከረብታው ፡ መስገጃዎች ፡ ለአጋንንቱም ፡ ለሠ ፲፮ ራቸውም ፡ እምቦሶች ፡ ካህናትን ፡ አቆመ ። ደግ

ሞም ፡ ለአባቶቻቸው ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይሠዉ ፡ ዘንድ ፡ ከእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመፈለግ ፡ ልባቸውን ፡ የሰጡ ፡ ሁሉ ፡ እነርሱን ፡ ተከትለው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጡ ። ፲፯ ሦስት ፡ ዓመትም ፡ በዳዊትና ፡ በሰሎሞን ፡ መንገድ ፡ ይሄዱ ፡ ነበርና ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ የይሁዳን ፡ መንግሥት ፡ አበረቱ ፣ የሰሎሞንንም ፡ ልጅ ፡ ሮብዓምን ፡ አጸኑ ።

፲፰ ሮብዓምም ፡ መሐላትን ፡ አገባ ፤ አባትዋ ፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ ኢያሪሙት ፡ ነበረ ፤ እናትዋም ፡ የእሴይ ፡ ልጅ ፡ የኤልያብ ፡ ልጅ ፡ አቢካኢል ፡ ፲፱ ነበረች ። እርስዋም ፡ የዑስን ፣ ሰማራያን ፣ ዘሃ ፳ ምን ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ ወለደችለት ። ከእርስዋም ፡ በኋላ ፡ የአቤሴሎምን ፡ ልጅ ፡ መዓካን ፡ አገባ ፤ እርስዋም ፡ አብያን ፣ ዓታይን ፣ ዚዛን ፣ ፳፩ ሰሎሚትን ፡ ወለደችለት ። ሮብዓምም ፡ ከሚስቶቹና ፡ ከቁባቶቹ ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ የአቤሴሎምን ፡ ልጅ ፡ መዓካን ፡ ወደደ ፤ አሥራ ፡ ስምንትም ፡ ሚስቶችና ፡ ስድሳ ፡ ቁባቶች ፡ ነበሩት ፣ ሀያ ፡ ስምንት ፡ ወንዶችና ፡ ስድሳ ፡ ሴቶች ፡ ፳፪ ልጆች ፡ ወለደ ። ሮብዓምም ፡ ንጉሥ ፡ ያደርገው ፡ ዘንድ ፡ አስቦአልና ፡ የመዓካን ፡ ልጅ ፡ አብያን ፡ በወንድሞቹ ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ አድርጎ ፡ ፳፫ ሾመው ። ተጠበበም ፣ ልጆቹንም ፡ ሁሉ ፡ በይሁዳና ፡ በብንያም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ በምሽጉ ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ከፋፈላቸው ፤ ብዙም ፡ ምግብ ፡ ሰጣቸው ፤ ብዙም ፡ ሚስቶች ፡ ፈለገላቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ የሮብዓም ፡ መንግሥት ፡ በጸናች ፡ ጊዜ ፣ እርሱም ፡ በበረታ ፡ ጊዜ ፣ እርሱና ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፪ ሕግ ፡ ተዉ ። እግዚአብሔርን ፡ በድለዋልና ፡ ሮብዓም ፡ በነገሠ ፡ በአምስተኛው ፡ ዓመት ፡ የግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ሺሻቅ ፡ ሺህ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሰረገሎችና ፡ ስድሳ ፡ ሺህ ፡ ፈረሰኞች ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ፫ ኢየሩሳሌም ፡ ወጣ ። ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ከግብጽ ፡ ለመጣው ፡ ሕዝብ ፡ ቍጥር ፡ አልነበረውም ፤ እነርሱም ፡ የልብያ ፡ ሰዎች ፣ ሱካው ፬ ያን ፣ የኢትዮጵያ ፡ ሰዎችም ፡ ነበሩ ። ለይሁዳም ፡ የነበሩትን ፡ ምሽጎች ፡ ከተሞች ፡ ወሰደ ፣ ፭ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ መጣ ። ነቢዩም ፡ ሸማያ ፡ ወደ ፡ ሮብዓምና ፡ ከሺሻቅ ፡ ሸሽተው ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ተሰበሰቡበት ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ መሳፍንት ፡ መጥቶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እናንተ ፡ ተዋችሁኝ ፤ ስለዚህ ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ በሺሻቅ ፡ እጅ ፡ ፮ ተውኋችሁ ። የእስራኤልም ፡ መሳፍንትና ፡ ንጉሡ ፡— እግዚአብሔር ፡ ጻድቅ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ፯ ሰውነታቸውን ፡ አዋረዱ ። እግዚአብሔርም ፡ ሰውነታቸውን ፡ እንዳዋረዱ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡— ሰውነታቸውን ፡ አዋርደዋል ፤ አላጠፋቸውም ፤ ከጥቂት ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ አድናቸዋለሁ ፣ ቍጣዬም ፡ በሺሻቅ ፡ እጅ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ አይፈስስም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ፰ ለእኔ ፡ መገዛትንና ፡ ለምድር ፡ ነገሥታት ፡ መገዛትን ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ ይገዙለታል ፡ ሲል ፡ ወደ ፡ ሸማያ ፡ መጣ ።

፱ የግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ሺሻቅም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጣ ፣ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ መዛግብትና ፡ የንጉሡን ፡ ቤት ፡ መዛግብት ፡ ወሰደ ፤ ሁሉንም ፡ ወሰደ ፤ ደግሞም ፡ ሰሎሞን ፡ የሠራቸውን ፡ የወርቁን ፡ ጋሻዎች ፡ ወሰደ ። ፲ ንጉሡም ፡ ሮብዓም ፡ በእነርሱ ፡ ፋንታ ፡ የናስ ፡ ጋሻዎችን ፡ ሠራ ፣ የንጉሡንም ፡ ቤት ፡ ደጅ ፡ በሚጠብቁ ፡ በዘበኞች ፡ አለቃ ፡ እጅ ፡ አኖራቸው ። ፲፩ ንጉሡም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በገባ ፡ ቍጥር ፡ ዘበኞች ፡ መጥተው ፡ ይሸከሙአቸው ፡ ነበር ፣ መልሰውም ፡ በዘበኞች ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ፲፪ ያኖሩአቸው ፡ ነበር ። ሰውነቱንም ፡ ባዋረደ ፡ ጊዜ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ ፈጽሞ ፡ እንዳያጠፋው ፡ ከእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ተመለሰ ፤ በይሁዳም ፡ ደግሞ ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ተገኘ ።

፲፫ ንጉሡም ፡ ሮብዓም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በረታ ፡ ንጉሥም ፡ ሆነ ፤ ሮብዓምም ፡ በነገሠ ፡ ጊዜ ፡ የአርባ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ጐልማሳ ፡ ነበረ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ስሙን ፡ ያኖርባት ፡ ዘንድ ፡ ከእስራኤል ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ በመረጣት ፡ ከተማ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አሥራ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡ የአሞን ፡ ሴት ፡ ናዕማ ፡ ነበረች ። ፲፬ እግዚአብሔርንም ፡ ይሻ ፡ ዘንድ ፡ ልቡን ፡ አላዘጋጀም ፤ ነበርና ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረገ ።

፲፭ የሮብዓምም ፡ የፊተኛውና ፡ የኋለኛው ፡ ነገር ፡ በነቢዩ ፡ ሸማያና ፡ በባለ ፡ ራእዩ ፡ በአዶ ፡ የትውልድ ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? በሮብዓምና ፡ በኢዮርብዓም ፡ መካከልም ፡ ፲፮ በዘመናቸው ፡ ሁሉ ፡ ሰልፍ ፡ ነበረ ። ሮብዓምም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፣ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ተቀበረ ፤ ልጁም ፡ አብያ ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ ንጉሡም ፡ ኢዮርብዓም ፡ በነገሠ ፡ በአሥራ ፡ ስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ አብያ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ፪ ንጉሥ ፡ ሆነ ። ሦስት ፡ ዓመት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ነገሠ ፤ የእናቱም ፡ ስም ፡ ሚካያ ፡ ነበረ ፣ የገብዓ ፡ ሰው ፡ የኡርኤል ፡ ልጅ ፡ ነበረች ። ፫ በአብያና ፡ በኢዮርብዓም ፡ መካከልም ፡ ሰልፍ ፡ ነበረ ። አብያም ፡ የተመረጡትን ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ ኃያላን ፡ ሰልፈኞች ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ ወጣ ፤ ኢዮርብዓምም ፡ የተመረጡትን ፡ ስምንት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡ ሰዎች ፡ ይዞ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ፬ ተሰለፈ ። አብያም ፡ በተራራማው ፡ በኤፍሬም ፡ አገር ፡ ባለው ፡ በጽማራይም ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ኢዮርብዓምና ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ሆይ ፣ ስሙኝ ፤ ፭ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ መን

ግሥትን ፡ ለዳዊትና ፡ ለልጆቹ ፡ በጨው ፡ ቃል ፡
ኪዳን ፡ ለዘላለም ፡ እንደ ፡ ሰጠ ፡ በውኑ ፡ አታ
፮ ውቁምን ? የዳዊት ፡ ልጅ ፡ የሰሎሞን ፡ ባሪያ ፡
የናባጥ ፡ ልጅ ፡ ኢዮርብዓም ፡ ግን ፡ ተነሥቶ ፡
፯ በጌታው ፡ ላይ ፡ ዐመፀ ። ክፉዎች ፡ ሰዎችና ፡
ምናምንቴዎችም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተሰበሰቡ ፤ ሮብ
ዓም ፡ ሕፃንና ፡ ለጋ ፡ በነበረበት ፡ ጊዜ ፥ ሊቋቋማ
ቸውም ፡ ባልቻለበት ፡ ጊዜ ፥ በሰሎሞን ፡ ልጅ ፡
፰ በሮብዓም ፡ ላይ ፡ በረቱበት ። አሁንም ፡ በዳ
ዊት ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ የሚሆነውን ፡ የእግዚአብ
ሔርን ፡ መንግሥት ፡ ልትቋቋሙ ፡ ታስባላችሁ ።
እናንተም ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ሕዝብ ፡ ናችሁ ፥
ኢዮርብዓምም ፡ አማልክት ፡ አድርጎ ፡ የሠራ
ላችሁ ፡ የወርቅ ፡ እምቦሶች ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡
፱ ናቸው ። የአሮንን ፡ ልጆች ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ካህናትና ፡ ሌዋውያን ፡ አላሳደዳችሁምን ? እንደ ፡
ሌሎችም ፡ አሕዛብ ፡ ልማድ ፡ ካህናትን ፡ አላደ
ረጋችሁምን ? አንድ ፡ ወይፈንና ፡ ሰባት ፡ አውራ ፡
በጎች ፡ ይዞ ፡ ይቀድስ ፡ ዘንድ ፡ የሚመጣ ፡ ሁሉ ፡
አማልክት ፡ ላልሆኑት ፡ ለእነዚያ ፡ ካህን ፡ ይሆ
፲ ናል ። ለእኛ ፡ ግን ፡ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡
ነው ፥ አልተውነውም ፤ የእግዚአብሔርም ፡
አገልጋዮች ፡ የአሮን ፡ ልጆች ፡ ካህናቱ ፡ ሌዋ
ውያኑም ፡ በሥራቸው ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ናቸው ።
፲፩ በየጥዋቱና ፡ በየማታውም ፡ ለእግዚአብሔር ፡
የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ ጣፋጩን ፡
ዕጣን ፡ ያሳርጋሉ ፤ የገጹንም ፡ ኅብስት ፡ በን
ጹሕ ፡ ገበታ ፡ ላይ ፥ የወርቁን ፡ መቅረዝና ፡ ቀን
ዲሎቹንም ፡ ማታ ፡ ማታ ፡ እንዲያበሩ ፡ ያዘጋ
ጃሉ ፤ እኛም ፡ የአምላካችንን ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ትእዛዝ ፡ እንጠብቃለን ፥ እናንተ ፡ ግን ፡ ትታ
፲፪ ችሁታል ። እነሆም ፥ እግዚአብሔር ፡ በእኛ ፡
ላይ ፡ አለቃ ፡ ነው ፥ መለከቱንም ፡ የሚነፉ ፡
ካህናቱ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ናቸው ፥ በእናንተም ፡
ላይ ፡ ይጮኻሉ ። የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥
አይበጃችሁምና ፡ ከአባቶቻችሁ ፡ አምላክ ፡ ከእ
ግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ አትዋጉ ።
፲፫ ኢዮርብዓም ፡ ግን ፡ ድብቅ ፡ ጦር ፡ በስተ ፡
ኋላቸው ፡ አዘረ ፤ እነርሱ ፡ በይሁዳ ፡ ፊት ፡
ሆነው ፡ ድብቅ ፡ ጦሩ ፡ በስተ ፡ ኋላቸው ፡ ነበረ ።
፲፬ ይሁዳም ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ በተመለከተ ፡ ጊዜ ፥
እነሆ ፥ ሰልፉ ፡ በፊቱና ፡ በኋላው ፡ ነበረ ፤ ወደ ፡
እግዚአብሔርም ፡ ጮኹ ፥ ካህናቱም ፡ መለከ
፲፭ ቱን ፡ ነፉ ። የይሁዳም ፡ ሰዎች ፡ ጮኹ ፤ የይሁ
ዳም ፡ ሰዎች ፡ በጮኹ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡
ኢዮርብዓምንና ፡ እስራኤልን ፡ ሁሉ ፡ በአብያና ፡
፲፮ በይሁዳ ፡ ፊት ፡ መታቸው ። የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ ከይሁዳ ፡ ፊት ፡ ሸሹ ፥ እግዚአብሔ
፲፯ ርም ፡ በእጃቸው ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ። አብ
ያና ፡ ሕዝቡ ፡ ታላቅ ፡ አመታት ፡ መቱአቸው ፤
ከእስራኤልም ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ የተመ
፲፰ ረጡ ፡ ሰዎች ፡ ተገድለው ፡ ወደቁ ። በዚያም ፡
ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተዋረዱ ፥ የይሁ
ዳም ፡ ልጆች ፡ በአባቶቻቸው ፡ አምላክ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ታምነው ፡ ነበርና ፡ አሸነፉ ።
፲፱ አብያም ፡ ኢዮርብዓምን ፡ አሳደደው ፥ ከእር
ሱም ፡ ከተሞቹን ፥ ቤቴልንና ፡ መንደሮችዋን ፥
ይሻናንና ፡ መንደሮችዋን ፥ ዔፍሮንንና ፡ መን
፳ ደሮችዋን ፡ወሰደ ። ኢዮርብዓምም ፡ ከዚያ ፡
በኋላ ፡ በአብያ ፡ ዘመን ፡ አልበረታም ፤ እግዚአ
፳፩ ብሔርም ፡ ቀሠፈው ፥ ሞተም ። አብያም ፡ ጸና ፥
አሥራ ፡ አራትም ፡ ሚስቶች ፡ አገባ ፥ ሀያ ፡ ሁለ
ትም ፡ ወንዶች ፡ ልጆችንና ፡ አሥራ ፡ ስድስት ፡
፳፪ ሴቶች ፡ ልጆችን ፡ ወለደ ። የአብያም ፡ የቀረው ፡
ነገርና ፡ አካሄዱ ፡ የተናገራቸውም ፡ ቃሎች ፡
በነቢዩ ፡ በአዶ ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፈዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ አብያም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በዳ
ዊትም ፡ ከተማ ፡ ቀበሩት ፤ ልጁም ፡ አሳ ፡ በእ
ርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ። በእርሱም ፡ ዘመን ፡ ምድ
ሪቱ ፡ አሥር ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ ዐረፈች ።
፪ አሳም ፡ በአምላኩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
፫ መልካምና ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አደረገ ፤ የእንግዶቹ
ንም ፡ አማልክት ፡ መሠዊያ ፡ የኮረብታውንም ፡
መስገጃዎች ፡ አፈረሰ ፥ ሐውልቶቹንም ፡ ሰበረ ፥
፬ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶቹንም ፡ ቈረጠ ፤ የአባቶ
ቻቸውን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይሹ ፡
ዘንድ ፥ ሕጉንና ፡ ትእዛዙንም ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡
፭ ይሁዳን ፡ አዘዘ ። ከይሁዳም ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡
የኮረብታውን ፡ መስገጃዎችና ፡ የፀሐይ ፡ ምስ
ሎችን ፡ አስወገደ ፤ መንግሥቱም ፡ በእርሱ ፡
፮ ሥር ፡ በሰላም ፡ ተቀመጠች ። በይሁዳም ፡
ምሽጎች ፡ ከተሞችን ፡ ሠራ ፤ እግዚአብሔርም ፡
ዕረፍት ፡ ስለ ፡ ሰጠው ፡ ምድሪቱ ፡ ጸጥ ፡ ብላ ፡
ነበር ፥ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ሰልፍ ፡ አልነበረም ።
፯ ይሁዳንም ፦ እነዚህን ፡ ከተሞች ፡ እንሥራ ፥
ቅጥርም ፡ ግንብም ፡ መዝጊያም ፡ መወርወሪ
ያም ፡ እናድርግባቸው ፤ አምላካችንን ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ ስለ ፡ ፈለግነው ፡ ምድሪቱ ፡ ገና ፡ በፊ
ታችን ፡ ናት ፤ እኛ ፡ ፈልገነዋል ፥ እርሱም ፡ በዙ
ሪያችን ፡ ዕረፍት ፡ ሰጥቶናል ፡ አለ ። እነርሱም ፡
፰ ሠሩ ፡ አከናወኑም ። ለአሳም ፡ አላባሽ ፡ አግሬ ፡
ጋሻና ፡ ጦር ፡ የሚሸከሙ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡
የይሁዳ ፡ ሠራዊት ፥ ጋሻም ፡ የሚሸከሙ ፡ ቀስ
ትም ፡ የሚገትሩ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ሰማንያ ፡
ሺህ ፡ የብንያም ፡ ሰዎች ፡ ነበሩት ፤ እነዚህም ፡
ሁሉ ፡ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ።
፱ ኢትዮጵያዊውም ፡ ዝሪ ፡ አንድ ፡ ሚሊዮን ፡
ሰዎችና ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሰረገሎች ፡ ይዞ ፡ ወጣ
፲ ባቸው ፤ ወደ ፡ መሪሳም ፡ መጣ ። አሳም ፡ ሊጋ
ጠመው ፡ ወጣ ፥ በመሪሳም ፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡
፲፩ በጽፋታ ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ ተሰለፉ ። አሳም ፦
አቤቱ ፥ በብዙም ፡ ሆነ ፡ በጥቂቱ ፡ ማዳን ፡ አይ
ሳንህም ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ሆይ ፥ በአንተ ፡
ታምነናልና ፥ በስምህም ፡ በዚህ ፡ ታላቅ ፡
ወገን ፡ ላይ ፡ መጥተናልና ፡ እርዳን ፤ አቤቱ ፥
አምላካችን ፡ አንተ ፡ ነህ ፤ሰውም ፡ አያሸንፍህ ፡

ብሎ ፡ ወደ ፡ አምላኩ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
፲፪ ጮኸ ። እግዚአብሔርም ፡ በአሳና ፡ በይሁዳ ፡
ፊት ፡ ኢትዮጵያውያንን ፡ መታ ፤ ኢትዮጵያ
፲፫ ውያንም ፡ ሸሹ ። አሳም ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡
ያለው ፡ ሕዝብ ፡ እስከ ፡ ጌራራ ፡ ድረስ ፡ አሳደ
ዱአቸው ፤ ኢትዮጵያውያንም ፡ ፈጽመው ፡
እስኪጠፉ ፡ ድረስ ፡ ወደቁ ፥ በእግዚአብሔርና ፡
በሠራዊቱ ፡ ፊት ፡ ተሰብብረዋልና ፤ እጅግም ፡
፲፬ ብዙ ፡ ምርኮ ፡ ወሰዱ ። ከእግዚአብሔርም ፡
ዘንድ ፡ ታላቅ ፡ ድንጋጤ ፡ ስለ ፡ ወደቀባቸው ፡
በጌራራ ፡ ዙሪያ ፡ የነበሩትን ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡
መቱ ፤ በከተሞቹም ፡ ውስጥ ፡ እጅግ ፡ ብዝበዛ ፡
፲፭ ነበረና ፡ ከተሞቹን ፡ ሁሉ ፡ በዘበዙ ። የከብቶቹ
ንም ፡ በረት ፡ አፈረሱ ፤ እጅግ ፡ ብዙ ፡ በጎችንና ፡
ግመሎችንም ፡ ማረኩ ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡
ተመለሱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በዖዴድ ፡ ልጅ ፡
፪ በዓዛርያስ ፡ ላይ ፡ ሆነ ፤ አሳንም ፡ ሊገናኘው ፡
ወጣ ፥ እንዲህም ፡ አለው ፡— አሳ ፡ ይሁዳና ፡
ብንያም ፡ ሁሉ ፡ ሆይ ፥ ስሙኝ ፤ እናንተ ፡ ከእ
ግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ ስትሆኑ ፡ እርሱ ፡ ከእናንተ ፡
ጋር ፡ ነው ፤ ብትፈልጉትም ፡ ይገኝላችኋል ፤
፫ ብትተዉት ፡ ግን ፡ ይተዋችኋል ። እስራኤልም ፡
ብዙ ፡ ዘመን ፡ ያለ ፡ እውነተኛ ፡ አምላክ ፥ ያለ ፡
አስተማሪም ፡ ካህን ፥ ያለ ፡ ሕግም ፡ ይኖሩ ፡ ነበር ።
፬ በመከራቸውም ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ አምላክ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተመልሰው ፡ በፈለጉት ፡
፭ ጊዜ ፡ አገኙት ። በዚያም ፡ ዘመን ፡ ለሚወጣ
ውና ፡ ለሚገባው ፡ ሰላም ፡ አልነበረም ፥ በምድ
ርም ፡ በሚኖሩት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ድን
፮ ጋጤ ፡ ነበረ ። እግዚአብሔር ፡ በመከራው ፡
ሁሉ ፡ ያስጨንቃቸው ፡ ነበርና ፡ ወገን ፡ ከወገን ፡
ጋር ፥ ከተማም ፡ ከከተማ ፡ ጋር ፡ ይዋጋ ፡ ነበር ።
፯ እናንተ ፡ ግን ፡ ለሥራችሁ ፡ ብድራት ፡ ይሆንላ
ችኋልና ፡ በርቱ ፥ እጃችሁም ፡ አይላላ ።
፰ አሳም ፡ ይህን ፡ ቃልና ፡ የነቢዩን ፡ የዖዴድን ፡
ትንቢት ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ልቡ ፡ ጸና ፥ ከይሁዳና ፡
ከብንያምም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ በተራራማውም ፡
በኤፍሬም ፡ አገር ፡ ከያዛቸው ፡ ከተሞች ፡ ጸያ
ፉን ፡ ነገር ፡ አስወገደ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡
ፊት ፡ የነበረውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መሠ
፱ ዊያ ፡ አደሰ ። አምላኩም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእ
ርሱ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ ከእስራ
ኤል ፡ ዘንድ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተጠ
ግተው ፡ ነበርና ፡ እርሱ ፡ ይሁዳንና ፡ ብንያምን ፡
ሁሉ ፥ ከኤፍሬምና ፡ ከምናሴም ፡ ከስምዖንም ፡
መጥተው ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ የተቀመጡትን ፡
፲ ሰበሰበ ። አሳም ፡ በነገሠ ፡ በአሥራ ፡ አምስተ
ኛው ፡ ዓመት ፡ በሦስተኛው ፡ ወር ፡ በኢየሩሳ
፲፩ ሌም ፡ ተሰበሰቡ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ካመጡት ፡
ምርኮ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ በሬዎችና ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡
፲፪ በጎች ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሠዉ ። በፍጹም ፡
ልባቸውና ፡ በፍጹም ፡ ነፍሳቸው ፡ የአባቶቻቸ
ውን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይሹ ፡ ዘንድ ፡
ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረጉ ፤ ፲፫ የእስራኤልንም ፡ አም
ላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የማይፈልግ ፥ ታናሽ ፡
ወይም ፡ ታላቅ ፥ ወንድ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ቢሆን ፥
ይገደል ፡ ዘንድ ፡ ማሉ ። ፲፬ ለእግዚአብሔርም ፡
በታላቅ ፡ ድምፅና ፡ በእልልታ ፥ በእምቢልታና ፡
በቀንደ ፡ መለከት ፡ ማሉ ። ፲፭ በፍጹምም ፡ ልባ
ቸው ፡ ምለዋልና ፥ በፍጹምም ፡ ሕሊናቸው ፡
ፈልገውታልና ፥ እርሱም ፡ ተገኝቶላቸዋልና ፡
ይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ በመሐላው ፡ ደስ ፡ አላቸው ፤ እግ
ዚአብሔርም ፡ በዙሪያቸው ፡ ዕረፍት ፡ ሰጣቸው ።
፲፮ ንጉሡም ፡ አሳ ፡ እናቱን ፡ መዓካን ፡ በማምለ
ኪያ ፡ ዐፀድ ፡ ጣዖት ፡ ስላደረገች ፡ ከእቴጌነትዋ ፡
አዋረዳት ፤ አሳም ፡ ምስልዋን ፡ ቈርጦ ፡ ቀጠቀ
ጠው ፥ በቄድሮንም ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ አቃጠ
ለው ። ፲፯ በኮረብታ ፡ ላይ ፡ የነበሩትን ፡ መስገጃ
ዎች ፡ ግን ፡ ከእስራኤል ፡ አላራቀም ፤ ይሁን ፡
እንጂ ፡ የአሳ ፡ ልብ ፡ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ ፍጹም ፡
ነበረ ። ፲፰ አባቱም ፡ የቀደሰውን ፥ እርሱም ፡ የቀ
ደሰውን ፡ ወርቁንና ፡ ብሩን ፥ ልዩ ፡ ልዩውንም ፡
ዕቃ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አገባ ።
፲፱ አሳም ፡ እስከ ፡ ነገሠበት ፡ እስከ ፡ ሠላሳ ፡ አም
ስተኛው ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ሰልፍ ፡ አልነበረም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ አሳ ፡ በነገሠ ፡ በሠላሳ ፡ ስድስተኛው ፡ ዓመት ፡
የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ባኦስ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡
ወጣ ፥ ወደ ፡ ይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ አሳ ፡
ማንም ፡ መውጣትና ፡ መግባት ፡ እንዳይችል ፡
ራማን ፡ ሠራ ። ፪ አሳም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቤትና ፡
ከንጉሡ ፡ ቤት ፡ መዝገብ ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡
ወስዶ ፡— ፫ በአባቴና ፡ በአባትህ ፡ መካከል ፡ እንደ ፡
ነበረው ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ በእኔና ፡ በአንተ ፡ መካ
ከል ፡ ይሆናል ፤ እነሆ ፥ ብርና ፡ ወርቅ ፡ ሰድጄ
ልሃለሁ ፤ እርሱ ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ እንዲርቅ ፡
ሄደህ ፡ ከእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ከባኦስ ፡ ጋር ፡
ያለህን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አፍርስ ፡ ብሎ ፡ በደማ
ስቆ ፡ ወደ ፡ ተቀመጠው ፡ ወደ ፡ ሶርያ ፡ ንጉሥ ፡
ወደ ፡ ወልደ ፡ አዴር ፡ ሰደደ ። ፬ ወልደ ፡ አዴ
ርም ፡ ንጉሡን ፡ አሳን ፡ እሺ ፡ አለው ፥ የሠራ
ዊቱንም ፡ አለቆች ፡ በእስራኤል ፡ ከተሞች ፡
ላይ ፡ ሰደደ ፤ እነርሱም ፡ ዒዮንንና ፡ ዳንን ፡ አቤ
ልማይምንና ፡ የንፍታሌምን ፡ የዕቃ ፡ ቤት ፡
ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ መቱ ። ፭ ባኦስም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡
ራማን ፡ መሥራት ፡ ተወ ፥ ሥራውንም ፡ አቋ
ረጠ ። ፮ ንጉሡም ፡ አሳ ፡ የይሁዳን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
ሰበሰበ ፤ ባኦስ ፡ ይሠራበት ፡ የነበረውን ፡ የራ
ማን ፡ ድንጋይና ፡ እንጨት ፡ አስወገዱ ፥ እር
ሱም ፡ ጌባንና ፡ ምጽጳን ፡ ሠራበት ።
፯ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ባለ ፡ ራእዩ ፡ አናኒ ፡ ወደ ፡
ይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ አሳ ፡ መጥቶ ፡ እንዲህ ፡
አለው ፡— በሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ ታምነሃልና ፥ በአ
ምላክህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ አልታመንህምና ፡

ስለዚህ ፡ የሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ ጭፍራ ፡ ከእጅህ ፡
፰ ፡ አምልጦአል ። ኢትዮጵያውያንና ፡ የልብያ ፡
ሰዎች ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ሰረገሎችና ፡ ፈረሰኞች ፡
የነበሩአቸው ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ጭፍራ ፡ አልነ
በሩምን ? በእግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ታመንህ ፡
፱ ፡ በእጅህ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ። እግዚአብሔር ፡
ልቡ ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ፍጹም ፡ የሆነውን ፡
ያጸና ፡ ዘንድ ፡ ዓይኖቹ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡
ይመለከታሉና ። አሁንም ፡ ስንፍና ፡ አድርገ
ሃል ፥ ስለዚህም ፡ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ ሰልፍ ፡ ይሆን
፲ ፡ ብሃል ። አሳም ፡ በባለ ፡ ራእዩ ፡ ላይ ፡ ተቈጣ ፤
ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ተቈጥቶአልና ፡ በግዞት ፡ አኖ
ረው ፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ አሳ ፡ ከሕዝቡ ፡ አያሌ ፡
ሰዎችን ፡ አስጨነቀ ።

፲፩ ፡ የአሳም ፡ የፊተኛውና ፡ የኋለኛው ፡ ነገር ፥
እነሆ ፥ በይሁዳና ፡ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ መጽ
፲፪ ፡ ሐፍ ፡ ተጽፎአል ። በነገሠም ፡ በሠላሳ ፡ ዘጠኝ
ኛው ፡ ዓመት ፡ አሳ ፡ እግሩን ፡ ታመመ ፤ ደዌ
ውም ፡ ጸናበት ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በታመመ ፡ ጊዜ ፡
ባለ ፡ መድኃኒቶችን ፡ እንጂ ፡ እግዚአብሔርን ፡
፲፫ ፡ አልፈለገም ። አሳም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀ
ላፋ ፥ በነገሠም ፡ በአርባ ፡ አንደኛው ፡ ዓመት ፡
፲፬ ፡ ሞተ ። ለእርሱም ፡ ለራሱ ፡ በሠራው ፡ መቃ
ብር ፡ በዳዊት ፡ ከተማ ፡ ቀበሩት ፤ በቀማሚ ፡
ብልሃት ፡ የተሰናዳ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ መልከም ፡
ሽቱ ፡ በተሞላ ፡ አልጋ ፡ ላይም ፡ አኖሩት ፤ እጅ
ግም ፡ ታላቅ ፡ የሆነ ፡ የመቃብር ፡ ወግ ፡ አደ
ረጉለት ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ ፡ በእርሱም ፡ ፋንታ ፡ ልጁ ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ ነገሠ ፥
፪ ፡ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ጠነከረ ። በተመሸጉትም ፡
በይሁዳ ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ወታደሮችን ፡ አኖረ ፥
በይሁዳም ፡ አገር ፡ አባቱም ፡ አሳ ፡ በወሰዳቸው ፡
በኤፍሬም ፡ ከተሞች ፡ ዘበኞችን ፡ አስቀመጠ ።
፫ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ከኢዮሣፍጥ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፥
በፊተኛይቱ ፡ በአባቱ ፡ በዳዊት ፡ መንገድ ፡ ሄደ
፬ ፡ አልና ፥ በአሊምንም ፡ አልፈለገምና ፤ ነገር ፡
ግን ፡ የአባቱን ፡ አምላክ ፡ ፈለገ ፥ በትእዛዙም ፡
ሄደ ፥ የእስራኤልንም ፡ ሥራ ፡ አልሠራም ።
፭ ፡ እግዚአብሔርም ፡ መንግሥቱን ፡ በእጁ ፡ አጸና ፤
ይሁዳም ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ለኢዮሣፍጥ ፡
አመጣ ፤ እጅግም ፡ ብዙ ፡ ብልጥግናና ፡ ክብር ፡
፮ ፡ ሆነለት ። ልቡም ፡ በእግዚአብሔር ፡ መንገድ ፡
ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ፤ የኮረብታውን ፡ መስገጃዎ
ችና ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀዱንም ፡ ከይሁዳ ፡ አስ
ወገደ ።

፯ ፡ በነገሠም ፡ በሦስተኛው ፡ ዓመት ፡ በይሁዳ ፡
ከተሞች ፡ ያስተምሩ ፡ ዘንድ ፡ መሳፍንቱን ፥ ቤን
ኃይልን ፥ አብድያስን ፥ ዘካርያስን ፥ ናትናኤ
፰ ፡ ልን ፥ ሚክያስን ፥ ሰደደ ። ከእነርሱም ፡ ጋር ፡
ሌዋውያንን ፡ ሸማያን ፥ ነታንያን ፥ ዝባድያን ፥
አሣሄልን ፥ ሰሚራሞትን ፥ ዮናትንን ፥ አዶንያ
ስን ፥ ጦብያን ፥ ጦባዶንያን ፡ ሰደደ ፡ ከእነር
ሱም ፡ ጋር ፡ ካህናቱን ፡ ኤሊሳማንና ፡ ኢዮራ
፱ ፡ ምን ፡ ሰደደ ። እነርሱም ፡ የእግዚአብሔርን ፡
የሕጉን ፡ መጽሐፍ ፡ ይዘው ፡ በይሁዳ ፡ ያስተ
ምሩ ፡ ነበር ፤ ወደ ፡ ይሁዳም ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡
ሄደው ፡ ሕዝቡን ፡ ያስተምሩ ፡ ነበር ።

፲ ፡ በይሁዳም ፡ ዙሪያ ፡ በነበሩ ፡ መንግሥታት ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ድንጋጤ ፡
ሆነ ፥ ከኢዮሣፍጥም ፡ ጋር ፡ አልተዋጉም ።
፲፩ ፡ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ ለኢዮሣፍጥ ፡ እጅ ፡
መንሻና ፡ የብር ፡ ግብር ፡ ያመጡ ፡ ነበሩ ፤ ዓረብ
ውያንም ፡ ደግሞ ፡ ከመንጎቻቸው ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡
ሰባት ፡ መቶ ፡ አውራ ፡ በጎችና ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡
ሰባት ፡ መቶ ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፡ ያመጡለት ፡
፲፪ ፡ ነበር ። ኢዮሣፍጥም ፡ እየበረታና ፡ እጅግም ፡
እየከበረ ፡ ሄደ ፤ በይሁዳም ፡ ግንቦችንና ፡ የጎ
፲፫ ፡ ተራ ፡ ከተሞችን ፡ ሠራ ። በይሁዳም ፡ ከተሞች ፡
ብዙ ፡ ሥራ ፡ ሠራ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ጽኑዓን ፡
፲፬ ፡ ኃያላን ፡ ሰልፈኞች ፡ ነበሩት ። ቍጥራቸውም ፡
እንደ ፡ አባቶቻቸው ፡ ቤት ፡ ይህ ፡ ነበረ ፤ ከይ
ሁዳ ፡ ሻለቆች ፡ አለቃው ፡ ዓድና ፥ ከእርሱም ፡
ጋር ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡
፲፭ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ አለቃው ፡
ይሆሐናን ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡
፲፮ ፡ ሰማንያ ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ ከእርሱም ፡
በኋላ ፡ በፈቃዱ ፡ ራሱን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የቀ
ደሰ ፡ የዝክሪ ፡ ልጅ ፡ ዓማስያ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡
ሁለት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡ ሰዎች ፡
፲፯ ፡ ነበሩ ። ከብንያምም ፡ ጽኑዕ ፡ ኃያል ፡ የነበረው ፡
ኤሊዳሄ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ቀስትና ፡ ጋሻ ፡ የሚ
፲፰ ፡ ይዙ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ ከእ
ርሱም ፡ በኋላ ፡ ዮዛባት ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ለሰ
ልፍ ፡ የተዘጋጁ ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡
፲፱ ፡ ነበሩ ። ንጉሡ ፡ በተመሸጉ ፡ በይሁዳ ፡ ከተ
ሞች ፡ ሁሉ ፡ ካኖራቸውም ፡ ሌላ ፡ እነዚህ ፡ ንጉ
ሡን ፡ ያገለግሉ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ ፡ ለኢዮሣፍጥም ፡ ብዙ ፡ ብልጥግናና ፡ ክብር ፡
፪ ፡ ነበረው ፤ ለአክዓብም ፡ ጋብቻ ፡ ሆነ ። ከጥቂት ፡
ዓመት ፡ በኋላም ፡ ወደ ፡ አክዓብ ፡ ወደ ፡ ሰማ
ርያ ፡ ወረደ ። አክዓብም ፡ ለእርሱና ፡ ከእርሱ ፡
ጋር ፡ ለነበሩት ፡ ሕዝብ ፡ ብዙ ፡ በጎችንና ፡ በሬ
ዎችን ፡ አረደ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ሬማት ፡
፫ ፡ ዘገለዓድ ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ አባበለው ። የእስራ
ኤልም ፡ ንጉሥ ፡ አክዓብ ፡ የይሁዳን ፡ ንጉሥ ፡
ኢዮሣፍጥን ፦ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ሬማት ፡
ዘገለዓድ ፡ ትሄዳለህን ? አለው ። እርሱም ፦
እኔ ፡ እንደ ፡ አንተ ፡ ነኝ ፥ ሕዝቤም ፡ እንደ ፡
ሕዝብህ ፡ ናቸው ፤ በሰልፍም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡
እንሆናለን ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።

፬ ፡ ኢዮሣፍጥም ፡ የእስራኤልን ፡ ንጉሥ ፦
የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አስቀድመህ ፡ ትጠ
፭ ፡ ይቅ ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለው ። የእ
ስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ነቢያቱን ፡ አራት ፡ መቶ ፡

ሰዎች ፡ ሰብስቦ ፡— ወደ ፡ ሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡
ለሰልፍ ፡ ልሂድን ? ወይስ ፡ ልቅር ? አላቸው ።
እነርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡ በንጉሥ ፡ እጅ ፡
፮ አሳልፎ ፡ ይሰጣታልና ፡ ውጣ ፡ አሉት ። ኢዮሣ
ፍጥ ፡ ግን ፡— እንጠይቀው ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአ
ብሔር ፡ ነቢይ ፡ የሆነ ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ በዚህ ፡ አይ
፯ ገኝምን ? አለ ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮ
ሣፍጥን ፡— እግዚአብሔርን ፡ የምንጠይቅበት ፡
አንድ ፡ ሰው ፡ አለ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ክፉ ፡
እንጂ ፡ ከቶ ፡ መልካም ፡ ትንቢት ፡ አይናገርል
ኝምና ፡ እጠላዋለሁ ፤ እርሱም ፡ የይምላ ፡ ልጅ ፡
ሚክያስ ፡ ነው ፡ አለው ። ኢዮሣፍጥም ፡—
፰ ንጉሥ ፡ እንዲህ ፡ አይበል ፡ አለው ። የእስራኤ
ልም ፡ ንጉሥ ፡ አንድ ፡ ጃንደረባ ፡ ጠርቶ ፡—
የይምላን ፡ ልጅ ፡ ሚክያስን ፡ ፈጥነህ ፡ አም
፱ ጣው ፡ አለው ። የእስራኤል ፡ ንጉሥና ፡ የይ
ሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ ልብሰ ፡ መንግሥት ፡
ለብሰው ፡ በሰማርያ ፡ በር ፡ መግቢያ ፡ አጠገብ ፡
በአደባባይ ፡ በዙፋኖቻቸው ፡ ላይ ፡ ተቀምጠው ፡
ነበር ፤ ነቢያትም ፡ ሁሉ ፡ በፊታቸው ፡ ትንቢት ፡
፲ ይናገሩ ፡ ነበር ። የክንዓና ፡ ልጅ ፡ ሴዴቅያስም ፡
የብረት ፡ ቀንዶች ፡ ሠርቶ ፡— እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— ሶርያውያንን ፡ እስኪጠፉ ፡
፲፩ ድረስ ፡ በእነዚህ ፡ ትወጋለህ ፡ አለ ። ነቢያትም ፡
ሁሉ ፡— እግዚአብሔር ፡ በንጉሡ ፡ እጅ ፡ አሳ
ልፎ ፡ ይሰጣታልና ፡ ወደ ፡ ሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡
ሂድና ፡ ተከናወን ፡ እያሉ ፡ እንዲሁ ፡ ትንቢት ፡
ይናገሩ ፡ ነበር ።

፲፪ ሚክያስንም ፡ ሊጠራ ፡ የሄደ ፡ መልእክተኛ ፡—
እነሆ ÷ ነቢያት ፡ በአንድ ፡ አፍ ፡ ሆነው ፡ ለን
ጉሡ ፡ መልካም ፡ ይናገራሉ ፤ ቃልህም ፡ እንደ ፡
ቃላቸው ፡ እንዲሆን ፡ መልካም ፡ እንድትናገር ፡
፲፫ እለምንሃለሁ ፡ አለው ። ሚክያስም ፡— ሕያው ፡
እግዚአብሔርን ! አምላኬ ፡ የሚለውን ፡ እር
፲፬ ሱን ፡ እናገራለሁ ፡ አለ ። ወደ ፡ ንጉሡም ፡
በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሡ ፡— ሚክያስ ፡ ሆይ ÷
ወደ ፡ ሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡ ለሰልፍ ፡ እንሂድን ?
ወይስ ፡ እንቅር ? አለው ። እርሱም ፡— ውጣ ÷
ተከናወን ፤ በእጅህም ፡ አልፈው ፡ ይሰጣሉ ፡
፲፭ አለ ። ንጉሡም ፡— በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡
ከእውነት ፡ በቀር ፡ እንዳትነግረኝ ፡ ስንት ፡ ጊዜ ፡
፲፮ አምልሃለሁ ? አለው ። እርሱም ፡— እስራ
ኤል ፡ ሁሉ ፡ ጠባቂ ፡ እንደሌላቸው ፡ በጎች ፡
በተራሮች ፡ ላይ ፡ ተበትነው ፡ አየሁ ፤ እግዚአ
ብሔርም ፡— ለእነዚህ ፡ ጌታ ፡ የላቸውም ÷ እያ
ንዳንዱም ፡ በሰላም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ይመለስ ፡ አለ ፡
፲፯ ብሎ ፡ ተናገረ ። የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮሣፍ
ጥን ፡— ክፉ ፡ እንጂ ፡ መልካም ፡ ትንቢት ፡ አይ
፲፰ ናገርልኝም ፡ አላልሁህምን ? አለው ። ሚክያ
ስም ፡ አለ ፡— እንግዲህ ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ቃል ፡ ስሙ ፤ እግዚአብሔር ፡ በዙፋኑ ፡ ተቀ
ምጦ ÷ የሰማይም ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ በቀኙና ፡
፲፱ በግራው ፡ ቆመው ፡ አየሁ ። እግዚአብሔ
ርም ፡— ወጥቶ ፡ በሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡ ይወድቅ ፡
ዘንድ ፡ የእስራኤልን ፡ ንጉሥ ፡ አክዓብን ፡ የሚ
ያታልል ፡ ማን ፡ ነው ? አለ ። አንዱም ፡ እንደ
ዚህ ÷ ሌላውም ፡ እንደዚያ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ተናገረ ።
፳ መንፈስም ፡ መጣ ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡
ቆሞ ፡— እኔ ፡ አታልልዋለሁ ፡ አለ ። እግዚአ
፳፩ ብሔርም ፡— በምን ? አለው ። እርሱም ፡—
ወጥቼ ፡ በነቢያቱ ፡ ሁሉ ፡ አፍ ፡ ሐሰተኛ ፡ መን
ፈስ ፡ እሆናለሁ ፡ አለ ። እግዚአብሔርም ፡—
ታታልለዋለህ ፤ ይቀናሃል ፤ ውጣ ÷ እንዲህም ፡
፳፪ አድርግ ፡ አለ ። አሁንም ÷ እነሆ ÷ እግዚአብ
ሔር ፡ በእነዚህ ፡ በነቢያትህ ፡ አፍ ፡ ሐሰተኛ ፡
መንፈስን ፡ አድርጎአል ፤ እግዚአብሔርም ፡
በአንተ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ተናግሮብሃል ።

፳፫ የክንዓናም ፡ ልጅ ፡ ሴዴቅያስ ፡ ቀረበ ÷ ሚክያስ
ንም ፡ በጥፊ ፡ መታውና ፡— የእግዚአብሔር ፡
መንፈስ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይናገር ፡ ዘንድ ፡ በምን ፡
፳፬ መንገድ ፡ ከእኔ ፡ አለፈ ? አለ ። ሚክያስም ፡—
እነሆ ÷ በዚያ ፡ ቀን ፡ ልትሸሸግ ፡ ወደ ፡ እልፍ
፳፭ ኝህ ፡ ስትሄድ ፡ ታያለህ ፡ አለ ። የእስራኤልም ፡
ንጉሥ ፡— ሚክያስን ፡ ውሰዱ ÷ ወደ ፡ ከተማ
ይቱም ፡ አለቃ ፡ ወደ ፡ አሞን ÷ ወደ ፡ ንጉሡም ፡
፳፮ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢዮአስ ፡ መልሳችሁ ፡— ንጉሡ ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— በደኅና ፡ እስክመለስ ፡ ድረስ ፡
ይህን ፡ ሰው ፡ በግዞት ፡ አኑሩት ÷ የመከራም ፡
እንጀራ ፡ መግቡት ÷ የመከራም ፡ ውኃ ፡ አጠ
፳፯ ጡት ፡ በሉ ፡ አለ ። ሚክያስም ፡— በደኅና ፡
ብትመለስ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእኔ ፡ የተናገረ ፡
አይደለም ፡ አለ ። ደግሞም ፡— እናንተ ፡ ሕዝብ ፡
ሁሉ ÷ ስሙኝ ፡ አለ ።

፳፰ የእስራኤል ፡ ንጉሥና ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡
ኢዮሣፍጥ ፡ ወደ ፡ ሬማት ፡ ዘገለዓድ ፡ ወጡ ።
፳፱ የእስራኤል ፡ ንጉሥም ፡ ኢዮሣፍጥን ፡— ልብ
ሴን ፡ ለውጬ ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ እገባለሁ ፤ አንተ ፡
ግን ፡ ልብስህን ፡ ልበስ ፡ አለው ። የእስራኤ
ልም ፡ ንጉሥ ፡ ልብሱን ፡ለወጠ ÷ ወደ ፡ ሰል
፴ ፍም ፡ ገቡ ። የሶርያም ፡ ንጉሥ ፡ የሰረገሎቹን ፡
አለቆች ፡— ከእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ በቀር ፡ ትንሽ ፡
ቢሆን ፡ ወይም ፡ ትልቅ ፡ ከማናቸውም ፡ ጋር ፡
፴፩ አትጋጠሙ ፡ ብሎ ፡ አዝዞ ፡ ነበር ። የሰረገሎ
ችም ፡ አለቆች ፡ ኢዮሣፍጥን ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡—
የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ነው ፡ አሉ ÷ ሊጋጠሙ
ትም ፡ ከበቡት ፤ ኢዮሣፍጥ ፡ ግን ፡ ጮኸ ÷ እግ
ዚአብሔርም ፡ ረዳው ÷ አምላኩም ፡ ከእርሱ ፡
፴፪ መለሳቸው ። የሰረገሎቹም ፡ አለቆች ፡ የእስራ
ኤል ፡ ንጉሥ ፡ እንዳልሆነ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ እርሱን ፡
፴፫ ከማሳደድ ፡ ተመለሱ ። አንድ ፡ ሰውም ፡ ቀስ
ቱን ፡ በድንገት ፡ ገትሮ ፡ የእስራኤልን ፡ ንጉሥ ፡
በጥሩሩ ፡ መጋጠሚያ ፡ በኩል ፡ ሳምባውን ፡
ወጋው ። ሰረጋለኛውንም ፡— ተወግቻለሁና ፡
እጅህን ፡ ግታ ፡ ከሰልፍም ፡ ውስጥ ፡ አውጣኝ ፡
፴፬ አለው ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ሰልፍ ፡ በረታ ፤ የእ
ስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ በሶርያውያን ፡ ፊት ፡ እስከ ፡
ማታ ፡ ድረስ ፡ በሰረገላው ፡ ላይ ፡ ራሱን ፡ ይደ
ግፍ ፡ ነበር ፤ ፀሐይም ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ሞተ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩፤ የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ፪፤ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በደኅና ፡ ተመለሰ ። ባለ ፡ ራእዩ ፡ የአናኒ ፡ ልጅ ፡ ኢዩ ፡ ሊገናኘው ፡ ወጣ ፥ ንጉሡንም ፡ ኢዮሣፍጥን ፡— ከሐዲውን ፡ ታግዛለህን ? ወይስ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚጠሉትን ፡ ትወድዳለህን ? ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ቍጣ ፡ ሆኖብሃል ። ፫፤ ነገር ፡ ግን ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶቹን ፡ ከምድር ፡ አስወግደሃልና ፥ እግዚአብሔርንም ፡ ትፈልግ ፡ ዘንድ ፡ ልብህን ፡ አዘጋጅተሃልና ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ተገኝቶብሃል ፡ አለው ።

፬፤ ኢዮሣፍጥም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተቀመጠ ፤ ደግሞም ፡ ከቤርሳቤህ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ተራራማው ፡ እስከ ፡ ኤፍሬም ፡ አገር ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ ወጥቶ ፡ ወደ ፡ አባቶቻቸው ፡ አምላክ ፡ ፭፤ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መለሳቸው ። በምድር ፡ ላይ ፡ በተመሸጉት ፡ በይሁዳ ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ በእያንዳንዱ ፡ ከተማ ፡ ውስጥ ፡ ፈራጆች ፡ አኖረ ። ፮፤ ፈራጆቹንም ፡— ለእግዚአብሔር ፡ እንጂ ፡ ለሰው ፡ አትፈርዱምና ፥ እርሱም ፡ በፍርድ ፡ ነገር ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ነውና ፡ የምታደርጉትን ፡ ፯፤ ተመልከቱ ። አሁንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ይሁን ፤ በአምላካችንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ በደልና ፡ ለሰው ፡ ፊት ፡ ማድላት ፡ መማለጃም ፡ መውሰድ ፡ የለምና ፡ ሁሉን ፡ ተጠንቀቃችሁ ፡ አድርጉ ፡ አላቸው ።

፰፤ ኢዮሣፍጥም ፡ ከሌዋውያንና ፡ ከካህናት ፡ ከእስራኤልም ፡ የአባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፥ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ፍርድን ፡ እንዲፈርዱ ፡ ክርክርንም ፡ እንዲቈርጡ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ሾመ ። እነርሱም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተቀመጡ ። ፱፤ እንዲህም ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ፡— እንዲሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በመፍራት ፡ በቅንነትም ፡ በፍጹ ፲፤ ምም ፡ ልብ ፡ አድርጉ ። በከተሞቻቸውም ፡ ከተቀመጡት ፡ ከወንድሞቻችሁ ፡ በደምና ፡ በደም ፡ መካከል ፡ በሕግና ፡ በትእዛዝ ፡ በሥርዓትና ፡ በፍርድም ፡ መካከል ፡ ያለ ፡ ማናቸውም ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ቢመጣ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዳይበድሉ ፥ ቍጣም ፡ በእናንተና ፡ በወንድሞቻችሁ ፡ ላይ ፡ እንዳይመጣ ፡ አስጠንቅቁአቸው ፤ እንዲህም ፡ ብታደርጉ ፡ በደለኞች ፡ አትሆኑም ። ፲፩፤ እነሆም ፥ ለእግዚአብሔር ፡ በሚሆነው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ የካህናቱ ፡ አለቃ ፡ አማርያ ፥ በንጉሡም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ የይሁዳ ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ የይስማኤል ፡ ልጅ ፡ ዝባድያ ፡ በላያችሁ ፡ ተሾመዋል ፤ ሌዋውያኑም ፡ ደግሞ ፡ በፊታችሁ ፡ አለቆች ፡ ይሆናሉ ፤ በርትታችሁም ፡ አድርጉ ፥ እግዚአብሔርም ፡ መልካም ፡ ከሚያደርግ ፡ ጋር ፡ ይሁን ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የሞዓብና ፡ የአሞን ፡ ልጆች ፡ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ምዑናውያን ፡ ኢዮሣፍጥን ፡ ሊወጉ ፡ መጡ ። ፪፤ ወሬኞችም ፡ መጥተው ፡— ከባሕሩ ፡ ማዶ ፡ ከሶርያ ፡ ታላቅ ፡ ሠራዊት ፡ መጥቶብሃል ፤ እነሆም ፥ ዓይንጋዲ ፡ በተባለች ፡ በሐሴሶን ፡ ታማር ፡ ናቸው ፡ ብለው ፡ ለኢዮሣፍጥ ፡ ነገሩት ። ፫፤ ኢዮሣፍጥም ፡ ፈራ ፥ እግዚአብሔርንም ፡ ሊፈልግ ፡ ፊቱን ፡ አቀና ፤ በይሁዳም ፡ ሁሉ ፡ ጾም ፡ አወጀ ። ፬፤ ይሁዳም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይፈልግ ፡ ዘንድ ፡ ተከማቸ ፤ ከይሁዳ ፡ ከተሞችም ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ፡ መጡ ።

፭፤ ኢዮሣፍጥም ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ጉባኤ ፡ መካከል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ በአዲሱ ፡ አደባባይ ፡ ፊት ፡ ቆመ ፤ ፮፤ እንዲህም ፡ አለ ፡— አቤቱ ፡ የአባቶቻችን ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ በሰማይ ፡ ያለህ ፡ አምላክ ፡ አንተ ፡ አይደለህምን ? የአሕዛብንስ ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ የምትገዛ ፡ አንተ ፡ አይደለህምን ? ኃይልና ፡ ችሎታ ፡ በእጅህ ፡ ነው ፥ ሊቋቋምህም ፡ የሚችል ፡ የለም ። ፯፤ አምላካችን ፡ ሆይ ፥ በዚህ ፡ ምድር ፡ የነበሩትን ፡ አሕዛብ ፡ ከሕዝብህ ፡ ከእስራኤል ፡ ፊት ፡ ያሳደድህ ፥ ለወዳጅህም ፡ ለአብርሃም ፡ ዘር ፡ ለዘላለም ፡ የሰጠሃት ፡ አንተ ፡ አይደለህምን ? ፰፤ እነርሱም ፡ ተቀመጡባት ፥ ለስምህም ፡ መቅደስን ፡ ሠርተውባት ፡— ፱፤ ክፉ ፡ ነገር ፥ የፍርድ ፡ ሰይፍ ፡ ወይም ፡ ቸነፈር ፡ ወይም ፡ ራብ ፥ ቢመጣብን ፡ ስምህ ፡ ባለበት ፡ በዚህ ፡ ቤት ፡ ፊትና ፡ በፊትህ ፡ ቆመን ፡ በመከራችን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እንጮኻለን ፥ አንተም ፡ ሰምተህ ፡ ታድነናለህ ፡ አሉ ። ፲፤ አሁንም ፥ እነሆ ፥ እስራኤል ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፡ ያልፉባቸው ፡ ዘንድ ፡ ያልፈቀድህላቸው ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ፈቀቅ ፡ ብለው ፡ ያላጠፉአቸው ፥ የአሞንና ፡ የሞዓብ ፡ ልጆች ፡ የሴይ ፲፩፤ ርም ፡ ተራራ ፡ ሰዎች ፥ እነሆ ፥ ለወሮታችን ፡ ክፉ ፡ ይመልሱልናል ፤ ከሰጠኸንም ፡ ርስት ፡ ያወጡን ፡ ዘንድ ፡ መጥተዋል ። ፲፪፤ አምላካችን ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ አትፈርድባቸውምን ? ይህን ፡ የመጣብንን ፡ ታላቅ ፡ ወገን ፡ እንቃወም ፡ ዘንድ ፡ አንችልም ፤ የምናደርገውንም ፡ አናውቅም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ዓይኖቻችን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ናቸው ። ፲፫፤ የይሁዳም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ከሕፃናቶቻቸውና ፡ ከሚስቶቻቸው ፡ ከልጆቻቸውም ፡ ጋር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቆመው ፡ ነበር ።

፲፬፤ የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ ከአሳፍ ፡ ወገን ፡ በነበረው ፡ በሌዋዊው ፡ በማታንያ ፡ ልጅ ፡ በይዒኤል ፡ ልጅ ፡ በበናያስ ፡ ልጅ ፡ በዘካርያስ ፡ ልጅ ፡ በየሕዚኤል ፡ ላይ ፡ በጉባኤው ፡ መካከል ፡ መጣ ፤ ፲፭፤ እንዲህም ፡ አለ ፡— ይሁዳ ፡ ሁሉ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ የምትኖሩ ፥ አንተም ፡ ንጉሡ ፡ ኢዮሣፍጥ ፥ ስሙ ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላችኋል ፡— ሰልፉ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የእናንተ ፡ አይደለምና ፡ ከዚህ ፡ ታላቅ ፡ ወገን ፡ የተነሣ ፡ አትፍሩ ፥ አትደንግጡም ። ፲፮፤ ነገ ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ውረዱ ፤ እነሆ ፥ በጺጽ ፡ ዓቀበት ፡ ይወጣሉ ፤ በሸለቆውም ፡ መጨረሻ ፡ በይ

ሩኤል ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ታገኙአቸዋላችሁ ። ፲፯፤ እናንተ ፡ በዚህ ፡ ሰልፍ ፡ የምትዋጉ ፡ አይደላችሁም ፤ ይሁዳና ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ÷ ተሰለፉ ÷ ዝም ፡ ብላችሁ ፡ ቁሙ ÷ የሚሆነውንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መድኃኒት ፡ እዩ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ነውና ፡ አትፍሩ ÷ አትደንግጡም ÷ ነገም ፡ ውጡባቸው ። ፲፰፤ ኢዮሣፍጥም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ተደፋ ፤ ይሁዳም ፡ ሁሉ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ የሚኖሩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ወደቁ ÷ ለእግዚአብሔርም ፡ ሰገዱ ። ፲፱፤ ሌዋውያንም ÷ የቀዓት ፡ ልጆችና ፡ የቆሬ ፡ ልጆች ÷ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በእጅግ ፡ ታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ፡ ቆሙ ።

፳፤ ማልደውም ፡ ተነሡ ÷ ወደ ፡ ቴቁሔም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወጡ ፤ ሲወጡም ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ ቆመና ፡— ይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የምትኖሩ ፡ ሆይ ÷ ስሙኝ ፤ በአምላካችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እመኑ ÷ ትጸኑማላችሁ ፤ በነቢያቱም ፡ እመኑ ÷ ነገሩም ፡ ይሰላላችኋል ፡ አለ ። ፳፩፤ ከሕዝቡም ፡ ጋር ፡ ተማክሮ ፡ በሠራዊቱ ፡ ፊት ፡ የሚሄዱትን ፡— ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ የሚሉትንም ÷ ጌጠኛ ፡ ልብስም ፡ ለብሰው ፡ የሚያመሰግኑትን ÷ ለእግዚአብሔርም ፡ የሚዘምሩትን ፡ መዘምራን ፡ አቆመ ። ፳፪፤ ዝማሬውንና ፡ ምስጋናውንም ፡ በጀመሩ ፡ ጊዜ ፡ ይሁዳን ፡ ሊወጉ ፡ በመጡት ፡ በአሞንና ፡ በሞዓብ ፡ ልጆች ፡ በሴይርም ፡ ተራራ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ድብቅ ፡ ጦርን ፡ አመጣባቸው ፤ እነርሱም ፡ ተመቱ ። ፳፫፤ የአሞንና ፡ የሞዓብ ፡ ልጆችም ፡ በሴይር ፡ ተራራ ፡ በሚኖሩት ፡ ላይ ፡ ፈጽመው ፡ ይገድሉአቸው ፡ ዘንድ ÷ ያጠፉአቸውም ፡ ዘንድ ፡ ተነሥተውባቸው ፡ ነበር ፤ በሴይርም ፡ የሚኖሩትን ፡ ካጠፉ ፡ በኋላ ፡ እያንዳንዱ ፡ ባልንጀራውን ፡ ለማጥፋት ፡ ተረዳዳ ።

፳፬፤ የይሁዳም ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ግንብ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡን ፡ አዩ ፤ እነሆም ÷ በምድሩ ፡ ሁሉ ፡ ሬሳ ፡ ሞልቶ ፡ ነበር ÷ ያመለጠም ፡ ሰው ፡ አልነበረም ። ፳፭፤ ኢዮሣፍጥና ፡ ሕዝቡም ፡ ምርኮ ፡ ይወስዱ ፡ ዘንድ ፡ መጡ ፤ ብዙ ፡ ከብትና ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዕቃም ÷ ልብስም ÷ እጅግም ፡ ያማረ ፡ ዕቃ ፡ አገኙ ÷ በዘበዙትም ÷ ሁሉንም ፡ ይሸከሙ ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉም ፤ ከምርኮውም ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ እስከ ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ይበዘብዙ ፡ ነበር ። ፳፮፤ በአራተኛውም ፡ ቀን ፡ በበረከት ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ ተሰበሰቡ ÷ በዚያም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባረኩ ፤ ስለዚህም ፡ ያ ፡ ስፍራ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ የበረከት ፡ ሸለቆ ፡ ተባለ ። ፳፯፤ የይሁዳና ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ሰዎች ÷ በፊታቸውም ፡ ኢዮሣፍጥ ÷ እግዚአብሔር ፡ በጠላቶቻቸው ፡ ላይ ፡ ደስ ፡ አሰኝቶአቸዋልና ፡ በደስታ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ተመለሱ ። ፳፰፤ በበገናና ፡ በመሰንቆ ፡ በመለከትም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ገቡ ። ፳፱፤ እግዚአብሔር ፡ የእስራኤልን ፡ ጠላቶች ፡ እንደ ፡ ወጋ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ በምድር ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍርሃት ፡ ሆነ ። ፴፤ የኢዮሣፍጥም ፡ መንግሥት ፡ ጸጥ ፡ አለች ÷ አምላኩም ፡ በዙሪያው ፡ ካሉ ፡ አሳረፈው ።

፴፩፤ ኢዮሣፍጥም ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ነገሠ ፤ መንግሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜም ፡ የሠላሳ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ጐልማሳ ፡ ነበረ ÷ በኢየሩሳሌምም ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡ የሺልሒ ፡ ልጅ ፡ ዓዙባ ፡ ነበረች ። ፴፪፤ በአባቱም ፡ በአሳ ፡ መንገድ ፡ ሄደ ÷ ከእርሱም ፡ ፈቀቅ ፡ አላለም ፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ አደረገ ። ፴፫፤ ነገር ፡ ግን ፡ የኮረብታው ፡ መስገጃዎች ፡ አልተወገዱም ፤ ሕዝቡም ፡ ገና ፡ ልባቸውን ፡ ወደ ፡ አባቶቻቸው ፡ አምላክ ፡ አላዘጋጁም ፡ ነበር ። ፴፬፤ የቀረውም ፡ የፊተኛውና ፡ የኋለኛው ፡ የኢዮሣፍጥ ፡ ነገር ÷ እነሆ ÷ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ በሚገኘው ፡ በአናኒ ፡ ልጅ ፡ በኢዩ ፡ ታሪክ ፡ ተጽፎአል ።

፴፭፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ ሥራው ፡ እጅግ ፡ ክፉ ፡ ከሆነ ፡ ከእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ከአካዝያስ ፡ ጋር ፡ ተባበረ ። ፴፮፤ ወደ ፡ ተርሴስም ፡ የሚሄዱትን ፡ መርከቦች ፡ ያሠሩ ፡ ዘንድ ፡ አንድ ፡ ሆኑ ፤ መርከቦቹንም ፡ በዔጽዮንጋብር ፡ አሠሩ ። ፴፯፤ የመሬሳም ፡ ሰው ፡ የዶዳያ ፡ ልጅ ፡ አልዓዛር ፡— ከአካዝያስ ፡ ጋር ፡ ተባብረሃልና ፡ እግዚአብሔር ፡ ሥራህን ፡ አፍርሶታል ፡ ብሎ ፡ በኢዮሣፍጥ ፡ ላይ ፡ ትንቢት ፡ ተናገረ ። መርከቦቹም ፡ ተሰበሩ ÷ ወደ ፡ ተርሴስም ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩፤ ኢዮሣፍጥም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ÷ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ተቀበረ ፤ ልጁም ፡ ኢዮራም ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ። ፪፤ ለእርሱም ፡ የኢዮሣፍጥ ፡ ልጆች ፡ ዓዛርያስ ÷ ይሒኤል ÷ ዘካርያስ ÷ ዔዛርያስ ÷ ሚካኤል ÷ ሰፋጥያስ ፡ የሚባሉ ፡ ወንድሞች ፡ ነበሩት ፤ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ የኢዮሣፍጥ ፡ ልጆች ፡ ነበሩ ። ፫፤ አባታቸውም ፡ ብዙ ፡ ስጦታ ÷ ብርና ፡ ወርቅ ÷ የከበረም ፡ ዕቃ ÷ በይሁዳም ፡ የተመሸጉትን ፡ ከተሞች ፡ ሰጣቸው ፤ መንግሥቱን ፡ ግን ፡ የበኵር ፡ ልጁ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለኢዮራም ፡ ሰጠ ። ፬፤ ኢዮራምም ፡ በአባቱ ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ ተነሥቶ ፡ በጸና ፡ ጊዜ ፡ ወንድሞቹን ፡ ሁሉ ፡ ሌሎችንም ፡ የእስራኤልን ፡ መሳፍንት ፡ በሰይፍ ፡ ገደለ ። ፭፤ ኢዮራምም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሠላሳ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ጐልማሳ ፡ ነበረ ÷ በኢየሩሳሌምም ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። ፮፤ የአክዓብንም ፡ ልጅ ፡ አግብቶ ፡ ነበርና ፡ የአክዓብ ፡ ቤት ፡ እንዳደረገ ፡ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ መንገድ ፡ ሄደ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡

፯ አደረገ ። ነገር ፡ ግን ፡ ከዳዊት ፡ ጋር ፡ ስላደረ
ገው ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፥ ለእርሱና ፡ ለልጆቹም ፡
በዘመናት ፡ ሁሉ ፡ መብራት ፡ ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡
ስለ ፡ ሰጠው ፡ ተስፋ ፥ እግዚአብሔር ፡ የዳዊ
ትን ፡ ቤት ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ አልወደደም ።

፰ በእርሱም ፡ ዘመን ፡ ኤዶምያስ ፡ በይሁዳ ፡
፱ ላይ ፡ ዐመፀ ፥ ለራሱም ፡ ንጉሥ ፡ አነገሠ ። ኢዮ
ራምም ፡ ከአለቆቹና ፡ ከሰረገሎቹ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡
ተሻገረ ፤ በሌሊትም ፡ ተነሥቶ ፡ እርሱንና ፡ የሰ
ረገሎቹን ፡ አለቆች ፡ ከብበው ፡ የነበሩትን ፡ የኤ
፲ ዶምያስን ፡ ሰዎች ፡ መታ ። ኤዶምያስ ፡ ግን ፡
በይሁዳ ፡ ላይ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ዐመፀ ፥ በዚ
ያንም ፡ ዘመን ፡ ልብና ፡ ደግሞ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡
ዐመፀ ፥ የአባቶቹን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ ትቶ ፡ ነበርና ።

፲፩ ዳግምም ፡ በይሁዳ ፡ ተራሮች ፡ ላይ ፡ መስገጃዎ
ችን ፡ ሠራ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ የተቀመጡትን ፡
እንዲያመነዝሩ ፡ አደረጋቸው ፥ ይሁዳንም ፡ አሳ
፲፪ ተው ። ከነቢዩም ፡ ከኤልያስ ፡ እንዲህ ፡ የሚል ፡
ጽሕፈት ፡ መጣበት ፦ የአባትህ ፡ የዳዊት ፡
አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦
በአባትህ ፡ በኢዮሣፍጥ ፡ መንገድ ፡ በይሁዳም ፡
፲፫ ንጉሥ ፡ በአሳ ፡ መንገድ ፡ አልሄድህምና ፥ በእ
ስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ መንገድ ፡ ግን ፡ ሄደሃልና ፥
የአክዓብም ፡ ቤት ፡ እንዳደረገ ፡ ይሁዳንና ፡
በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩትን ፡ እንዲያመነዝሩ ፡
አድርገሃልና ፥ ከአንተም ፡ የሚሻሉትን ፡ የአባ
ትህን ፡ ቤት ፡ ወንድሞችህን ፡ ገድለሃልና ፥
፲፬ እነሆ ፥ እግዚአብሔር ፡ ሕዝብህንና ፡ ልጆች
ህን ፡ ሚስቶችህንም ፡ ያለህንም ፡ ሁሉ ፡ በታላቅ ፡
፲፭ መቅሠፍት ፡ ይቀሥፋል ። አንተም ፡ ከደዌው ፡
ጽናት ፡ የተነሣ ፡ አንጀትህ ፡ በየዕለቱ ፡ እስኪ
ወጣ ፡ ድረስ ፡ በክፉ ፡ የአንጀት ፡ ደዌ ፡ ትታመ
ማለህ ።

፲፮ እግዚአብሔርም ፡ የፍልስጥኤማውያንና ፡
በኢትዮጵያውያን ፡ አጠገብ ፡ የሚኖሩትን ፡ የዓረ
ባውያንን ፡ መንፈስ ፡ በኢዮራም ፡ ላይ ፡ አስነሣ ።
፲፯ ወደ ፡ ይሁዳም ፡ ወጡ ፥ አፈረሱአትም ፥ የንጉ
ሡንም ፡ ቤት ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፥ ወንዶች ፡ ልጆቹ
ንም ፡ ሴቶች ፡ ልጆቹንም ፡ ማረኩ ፤ ከታናሹም ፡
ልጅ ፡ ከአካዝያስ ፡ በቀር ፡ ልጅ ፡ አልቀረለትም ።

፲፰ ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ በማ
፲፱ ይፈወስ ፡ ደዌ ፡ አንጀቱን ፡ ቀሠፈው ። ከቀ
ንም ፡ ወደ ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ ከሁለት ፡
ዓመት ፡ በኋላ ፡ ከደዌው ፡ ጽናት ፡ የተነሣ ፡ አን
ጀቱ ፡ ወጣ ፥ በክፉም ፡ ደዌ ፡ ሞተ ። ሕዝቡም ፡
ለአባቶቹ ፡ ያደርገው ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ለእርሱ ፡
፳ የመቃብር ፡ ወግ ፡ አላደረገም ። መንገሥ ፡ በጀ
መረ ፡ ጊዜ ፡ የሠላሳ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ጐልማሳ ፡
ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡
ነገሠ ፤ ማንም ፡ ሳያዝንለት ፡ ሄደ ፤ በዳዊትም ፡
ከተማ ፡ እንጂ ፡ በነገሥታት ፡ መቃብር ፡ አል
ቀበሩትም ።

ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ በኢየሩሳሌም ፡ የነበሩትም ፡ ታናሹን ፡ ልጁን ፡
አካዝያስን ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ አነገሡት ። የመ
ጣባቸው ፡ የዓረብና ፡ የአሊማዞን ፡ የሽፍቶች ፡
ጭፍራ ፡ የእርሱን ፡ ታላቆች ፡ ገድለዋቸው ፡
ነበርና ። የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ የኢዮራም ፡ ልጅ ፡
፪ አካዝያስ ፡ ነገሠ ። አካዝያስም ፡ መንገሥ ፡ በጀ
መረ ፡ ጊዜ ፡ ዕድሜው ፡ አርባ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡
ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤
እናቱም ፡ ጎቶልያ ፡ የተባለች ፡ የዘንበሪ ፡ ልጅ ፡
፫ ነበረች ። እናቱም ፡ ክፉ ፡ ለማድረግ ፡ ትመክ
ረው ፡ ነበርና ፡ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ በአክዓብ ፡ ቤት ፡
፬ መንገድ ፡ ሄደ ። አባቱም ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ የአ
ክዓብ ፡ ቤት ፡ እንዳደረገ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ፤ እስኪጠፋ ፡ ድረስ ፡ መካ
፭ ሪዎች ፡ ነበሩትና ። በምክራቸውም ፡ ሄደ ፥
ከእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ከአክዓብ ፡ ልጅ ፡ ከኢ
ዮራም ፡ ጋር ፡ የሶርያን ፡ ንጉሥ ፡ አዛሄልን ፡ በሬ
ማት ፡ ዘገለዓድ ፡ ሊዋጋ ፡ ሄደ ፤ ሶርያውያንም ፡
፮ ኢዮራምን ፡ አቈሰሉት ። ከሶርያም ፡ ንጉሥ ፡
ከአዛሄል ፡ ጋር ፡ በተዋጋ ፡ ጊዜ ፡ ሶርያውያን ፡
በሬማት ፡ ያቈሰሉትን ፡ ቍስል ፡ ይታከም ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኢይዝራኤል ፡ ተመለሰ ፤ ታም
ሞም ፡ ነበርና ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ የኢዮራም ፡
ልጅ ፡ አካዝያስ ፡ የአክዓብን ፡ ልጅ ፡ ኢዮራ
ምን ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኢይዝራኤል ፡ ወረደ ።

፯ አካዝያስም ፡ ወደ ፡ ኢዮራም ፡ በመምጣቱ ፡
ይጠፋ ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ነበረ ፤
በመጣም ፡ ጊዜ ፡ ከኢዮራም ፡ ጋር ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ የአክዓብን ፡ ቤት ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡
ቀባው ፡ ወደ ፡ ናሜሲ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢዩ ፡ ወጣ ።
፰ ኢዩም ፡ በአክዓብ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ ፍርድን ፡ ሲፈ
ጽም ፡ የይሁዳን ፡ መሳፍንትና ፡ አካዝያስን ፡ ያገ
ለግሉ ፡ የነበሩትን ፡ የአካዝያስን ፡ ወንድሞች ፡
፱ ልጆች ፡ አግኝቶ ፡ ገደላቸው ። አካዝያስንም ፡
ፈለገው ፥ በሰማርያም ፡ ተሸሽጎ ፡ ሳለ ፡ አገኙት ፤
ወደ ፡ ኢዩም ፡ አምጥተው ፡ ገደሉትና ፦ በፍ
ጹም ፡ ልብ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የፈለገው ፡ የኢ
ዮሣፍጥ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ቀበሩት ። ከአ
ካዝያስም ፡ ቤት ፡ ማንም ፡ መንግሥትን ፡ ይይዝ ፡
ዘንድ ፡ የሚችል ፡ አልነበረም ።

፲ የአካዝያስም ፡ እናት ፡ ጎቶልያ ፡ ልጅዋ ፡ እንደ ፡
ሞተ ፡ በየች ፡ ጊዜ ፡ ተነሥታ ፡ የይሁዳን ፡ ቤት ፡
፲፩ መንግሥት ፡ ዘር ፡ ሁሉ ፡ አጠፋች ። የንጉሡ ፡
ልጅ ፡ ዮሳቤት ፡ ግን ፡ ከተገደሉት ፡ ከንጉሡ ፡
ልጆች ፡ መካከል ፡ የአካዝያስን ፡ ልጅ ፡ ኢዮአ
ስን ፡ ሰርቃ ፡ ወሰደች ፤ እርሱንና ፡ ሞግዚቱን ፡
በእልፍኝ ፡ ውስጥ ፡ አኖረቻቸው ፤ ጎቶልያ ፡
እንዳታስገድለው ፡ የንጉሡ ፡ የኢዮራም ፡ ልጅ ፡
የአካዝያስ ፡ እኅት ፡ የካህኑ ፡ የዮዳሄ ፡ ሚስት ፡
፲፪ ዮሳቤት ፡ እንዲሁ ፡ ሸሸገችው ። በእነርሱም ፡
ዘንድ ፡ ተሸሽጎ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ስድ

ስት ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ ተቀመጠ ፤ ጎቶልያም ፡
በምድር ፡ ላይ ፡ ነገሠች ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩፤ በሰባተኛውም ፡ ዓመት ፡ ዮዳሄ ፡ በረታ ፥
የመቶ ፡ አለቆቹንም ፥ የይሮሐምን ፡ ልጅ ፡ ዓዛ
ርያስን ፥ የይሆሐናንንም ፡ ልጅ ፡ ይስማኤልን ፥
የዖቤድንም ፡ ልጅ ፡ ዓዛርያስን ፥ የዓዳያንም ፡
ልጅ ፡ መዕሤያን ፥ የዝክሪንም ፡ ልጅ ፡ ኤሊሳ
ፋጥን ፡ ወስዶ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
፪፤ አደረገ ። ይሁዳንም ፡ ዞሩ ፥ በይሁዳም ፡ ከተ
ሞች ፡ ሁሉ ፡ ሌዋውያንንና ፡ የእስራኤልን ፡
አባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ሰብስበው ፡ ወደ ፡
፫፤ ኢየሩሳሌም ፡ መጡ ። ጉባኤውም ፡ ሁሉ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ከንጉሥ ፡ ጋር ፡
ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረገ ። ዮዳሄም ፡ አላቸው ፡—
እነሆ ፥ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ዳዊት ፡ ልጆች ፡
እንደ ፡ ተናገረ ፡ የንጉሡ ፡ ልጅ ፡ ይነግሣል ።
፬፤ የምታደርጉት ፡ ይህ ፡ ነው ፤ በሰንበት ፡ ቀን ፡
ከምትገቡት ፡ ከእናንተ ፡ ከካህናትና ፡ ከሌዋው
ያን ፡ ከሦስት ፡ አንድ ፡ እጅ ፡ በመግቢያ ፡ በሮች ፡
፭፤ በረኞች ፡ ሁኑ ፤ ከሦስት ፡ አንድ ፡ እጅም ፡
በንጉሥ ፡ ቤት ፡ ሁኑ ፤ አንድ ፡ እጅም ፡ በመካ
ከለኛው ፡ በር ፡ ሁኑ ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በእግዚ
፮፤ አብሔር ፡ ቤት ፡ አደባባይ ፡ ይሁኑ ። ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ግን ፡ ከካህናትና ፡ ከአገ
ልጋዮቹ ፡ ሌዋውያን ፡ በቀር ፡ ማንም ፡ አይግባ ፤
እነርሱ ፡ ቅዱሳን ፡ ናቸውና ፡ ይግቡ ፤ ሕዝቡም ፡
ሁሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ይጠብቅ ።
፯፤ ሌዋውያንም ፡ የጦር ፡ መሣሪያቸውን ፡ በእጃ
ቸው ፡ ይዘው ፡ ንጉሡን ፡ በዙሪያው ፡ ይከበ
ቡት ፤ ወደ ፡ ቤቱም ፡ የሚገባ ፡ ይገደል ፤ ንጉ
ሡም ፡ ሲገባና ፡ ሲወጣ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሁኑ ።
፰፤ ሌዋውያንና ፡ ይሁዳም ፡ ሁሉ ፡ ካህኑ ፡ ዮዳሄ ፡
ያዘዘውን ፡ ሁሉ ፡ አደረጉ ፤ ካህኑም ፡ ዮዳሄ ፡
ሰሞነኞቹን ፡ አላሰናበተም ፡ ነበርና ፡ እያንዳንዱ ፡
በሰንበት ፡ ቀን ፡ ይገቡ ፡ የነበሩትን ፡ በሰንበ
ትም ፡ ቀን ፡ ይወጡ ፡ የነበሩትን ፡ ሰዎች ፡ ወሰደ ።
፱፤ ካህኑም ፡ ዮዳሄ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የነበ
ረውን ፡ የንጉሡን ፡ የዳዊትን ፡ ጋሻና ፡ ጦር ፡
አላባሽ ፡ አግሬውንም ፡ ጋሻ ፡ ለመቶ ፡ አለቆች ፡
፲፤ ሰጣቸው ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ የጦር ፡
መሣሪያውን ፡ በእጁ ፡ እየያዘ ፡ በንጉሡ ፡ ዙሪያ ፡
ከቤቱ ፡ ቀኝ ፡ እስከ ፡ ቤቱ ፡ ግራ ፡ ድረስ ፡ በመ
ሠዊያውና ፡ በቤቱ ፡ አጠገብ ፡ እንዲቆም ፡ አደ
፲፩፤ ረገ ። የንጉሡንም ፡ ልጅ ፡ አውጥተው ፡ ዘው
ዱን ፡ ጫኑበት ፥ ምስክሩንም ፡ ሰጡት ፥ አነገ
ሡትም ፤ ዮዳሄና ፡ ልጆቹም ፡— ንጉሡ ፡ ሺህ ፡
ዓመት ፡ ይንገሥ ፡ እያሉ ፡ቀቡት ።
፲፪፤ ጎቶልያም ፡ የሚሮጡትንና ፡ ንጉሡን ፡ የሚ
ያመሰግኑትን ፡ የሕዝቡን ፡ ድምፅ ፡ በሰማች ፡
ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
፲፫፤ መጣች ። እነሆም ፥ ንጉሡ ፡ በመግቢያው ፡
በዓምዱ ፡ አጠገብ ፡ ሆኖ ፡ ከንጉሡም ፡ ጋር ፡
አለቆችና ፡ መለከተኞች ፡ ቆመው ፡ አየች ።
የአገሩም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ብሎአቸው ፡
መለከቱን ፡ ይነፉ ፡ ነበር ፤ መዘምራንም ፡ በዜማ ፡
ዕቃ ፡ እያዜሙ ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ፡ ይዘ
ምሩ ፡ ነበር ። ጎቶልያም ፡ ልብስዋን ፡ ቀድዳ ፡—
ዓመፅ ፡ ነው ፥ ዓመፅ ፡ ነው ፡ ብላ ፡ ጮኸች ።
፲፬፤ ካህኑም ፡ ዮዳሄ ፡ በጭፍራው ፡ ላይ ፡ የተሾሙ
ትን ፡ የመቶ ፡ አለቆች ፡— ወደ ፡ሰልፉ ፡ መካከል ፡
አውጡአት ፤ የሚከተላትም ፡ በሰይፍ ፡ ይገደል ፡
ብሎ ፡ አዘዛቸው ። ካህኑም ፡— በእግዚአብ
ሔር ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ አትግደሉአት ፡ አለ ።
፲፭፤ ገለልም ፡ ብለው ፡ አሳለፉአት ፤ እርስዋም ፡ ወደ ፡
ፈረሱ ፡ በር ፡ መግቢያ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቤት ፡
ሄደች ፥ በዚያም ፡ ገደሉአት ።
፲፮፤ ዮዳሄም ፡ በእርሱና ፡ በሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ በንጉ
ሡም ፡ መካከል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡
፲፯፤ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረገ ። ሕዝ
ቡም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ በኣል ፡ ቤት ፡ ሄደው ፡ አፈ
ረሱት ፥ መሠዊያዎቹንና ፡ ምስሎቹንም ፡ አደ
ቀቁ ፥ የበኣልንም ፡ ካህን ፡ ማታንን ፡ በመሠዊ
፲፰፤ ያው ፡ ፊት ፡ ገደሉት ። ዮዳሄም ፡ በሙሴ ፡
ሕግ ፡ እንደ ፡ ተጻፈው ፥ እንደ ፡ ዳዊትም ፡ ትእ
ዛዝ ፥ በደስታና ፡ በመዝሙር ፡ ለእግዚአብሔር ፡
የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡
ዳዊት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የከፈላቸውን ፡
ካህናትና ፡ ሌዋውያን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
፲፱፤ አገልግሎት ፡ ላይ ፡ ሾመ ። በማናቸውም ፡ ነገር ፡
ሁሉ ፡ ርኩስ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ እንዳይገባ ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በር ፡ በረኞችን ፡ አኖረ ።
፳፤ የመቶ ፡ አለቆችንም ፥ ከበርቴዎቹንም ፥ የሕ
ዝቡንም ፡ አለቆች ፥ የአገሩንም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡
ወሰደ ፥ ንጉሡንም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
አወረደ ፤ በላይኛውም ፡ በር ፡ በኩል ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ ቤት ፡ መጡ ፥ ንጉሡንም ፡ በመንግ
፳፩፤ ሥቱ ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ አኖሩት ። የአገሩም ፡
ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ አላቸው ፥ ከተማይቱም ፡
ጸጥ ፡ አለች ፤ ጎቶልያንም ፡ በሰይፍ ፡ ገደሉአት ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩፤ ኢዮአስም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሰ
ባት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡
አርባ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱ ፡ ሳብያ ፡ የተባ
፪፤ ለች ፡ የቤርሳቤህ ፡ ሴት ፡ ነበረች ። በካህኑም ፡
በዮዳሄ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ኢዮአስ ፡ በእግዚአብ
፫፤ ሔር ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አደረገ ። ዮዳሄም ፡
ሁለት ፡ ሚስቶች ፡ አጋባው ፤ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡
ልጆችንም ፡ ወለደ ።
፬፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ኢዮአስ ፡ የእግዚአብሔ
፭፤ ርን ፡ ቤት ፡ ይጠግን ፡ ዘንድ ፡ አሰበ ። ካህናት
ንና ፡ ሌዋውያንንም ፡ ሰብስቦ ፡— ወደ ፡ ይሁዳ ፡
ከተሞች ፡ ውጡ ፥ የአምላካችሁንም ፡ ቤት ፡
በየዓመቱ ፡ ለማደስ ፡ ከእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ገንዘ
ብን ፡ ሰብስቡ ፤ ነገሩንም ፡ ፈጥናችሁ ፡ አድ
ርጉ ፡ አላቸው ። ሌዋውያን ፡ ግን ፡ ቸል ፡ አሉ ።

፮ ንጉሡም ፡ አለቃውን ፡ ዮዳሄን ፡ ጠርቶ ፡— የእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ ስለ ፡ ምስክሩ ፡ ድንኳን ፡ የእስራኤል ፡ ጉባኤ ፡ እንዲያዋጣ ፡ ያዘዘውን ፡ ግብር ፡ ከይሁዳና ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ሌዋውያንን ፡ አላተጋሃቸውም ? አለው ። ፯ ጎቶልያ ፡ ከሐዲት ፡ ነበረችና ፡ ልጆችዋም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ አፍርሰዋልና ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ተቀድሶ ፡ የነበረውን ፡ ሁሉ ፡ ለበኣሊም ፡ ሰጥተዋልና ።

፰ ንጉሡም ፡ አዘዘ ፥ ሣጥንም ፡ ሠርተው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በር ፡ አጠገብ ፡ በስተ ፡ ውጭ ፡ አኖሩት ። ፱ የእግዚአብሔርም ፡ ባሪያ ፡ ሙሴ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ያዘዘውን ፡ ግብር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አዋጅ ፡ ነገሩ ። ፲ አለቆችና ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ብሎአቸው ፡ አቀረቡት ፥ እስኪሞላም ፡ ድረስ ፡ በሣጥኑ ፡ ውስጥ ፡ ጣሉት ። ፲፩ ሣጥኑም ፡ በሌዋውያን ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ሹማምት ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፥ ብዙ ፡ ገንዘብም ፡ እንዳለበት ፡ በየ ፡ ጊዜ ፥ የንጉሡ ፡ ጸሐፊና ፡ የዋነኛው ፡ ካህን ፡ ሹም ፡ እየመጡ ፡ ብሩን ፡ ከሣጥን ፡ ያወጡ ፡ ነበር ፥ ሣጥኑንም ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ይመልሱት ፡ ነበር ። እንዲሁም ፡ በየቀኑ ፡ ያደርጉ ፡ ነበር ፥ ብዙም ፡ ገንዘብ ፡ አከማቹ ። ፲፪ ንጉሡና ፡ ዮዳሄም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ ለተሾሙት ፡ ሰጡአቸው ፤ እነርሱም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ የሚጠግኑትን ፡ ጠራቢዎችንና ፡ አናጢዎችን ፥ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ የሚያድሱትን ፡ የብረትና ፡ የናስ ፡ ሠራተኞችን ፡ ይገዙበት ፡ ነበር ። ፲፫ ሠራተኞችም ፡ ሠሩ ፥ የፈረሰውም ፡ በእጃቸው ፡ ተጠገነ ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ሥራ ፡ መለሱ ፥ አጽንተውም ፡ አቆሙት ። ፲፬ በጨረሱም ፡ ጊዜ ፡ የተረፈውን ፡ ገንዘብ ፡ በንጉሡና ፡ በዮዳሄ ፡ ፊት ፡ አመጡ ፤ እነርሱም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ዕቃ ፥ ለአገልግሎትና ፡ ለቍርባን ፡ ዕቃ ፥ ለጭልፋዎችም ፥ ለወርቅና ፡ ለብርም ፡ ዕቃ ፡ አደረጉት ። በዮዳሄም ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ሁልጊዜ ፡ ያቀርቡ ፡ ነበር ።

፲፭ ዮዳሄም ፡ ሸመገለ ፥ ዕድሜም ፡ ጠግቦ ፡ ሞተ ፤ በሞቱ ፡ ጊዜ ፡ ዕድሜው ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ነበረ ። ፲፮ ከእስራኤልም ፡ ጋር ፥ ከእግዚአብሔርና ፡ ከቤቱም ፡ ጋር ፡ ቸርነት ፡ ሠርቶአልና ፡ በዳዊት ፡ ከተማ ፡ ከነገሥታቱ ፡ ጋር ፡ ቀበሩት ። ፲፯ ዮዳሄም ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ የይሁዳ ፡ አለቆች ፡ ገብተው ፡ ለንጉሡ ፡ እጅ ፡ ነሡ ፤ ንጉሡም ፡ እሺ ፡ አላቸው ። ፲፰ የአባቶቻቸውንም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትተው ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶችንና ፡ ጣዖታትን ፡ አመለኩ ፤ በዚህ ፡ በደላቸውም ፡ ምክንያት ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ ቍጣ ፡ ወረደ ። ፲፱ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ይመልሱአቸው ፡ ዘንድ ፡ ነቢያትን ፡ ይሰድድላቸው ፡ ነበር ፤ መሰከሩባቸውም ፥ እነርሱ ፡ ግን ፡ አላደመጡም ።

፳ የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በካህኑ ፡ በዮዳሄ ፡ ልጅ ፡ በዘካርያስ ፡ ላይ ፡ መጣ ፤ እርሱም ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ ቆመና ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ለምን ፡ ትተላለፋላችሁ ? መልካምም ፡ አይሆንላችሁም ፤ እግዚአብሔርን ፡ ስለ ፡ ተዋችሁ ፡ እርሱ ፡ ትቶአችኋል ፡ አላቸው ። ፳፩ ተማማሉበትም ፡ በንጉሡም ፡ ትእዛዝ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አደባባይ ፡ ውስጥ ፡ በድንጋይ ፡ ወገሩት ። ፳፪ እንዲሁም ፡ ንጉሡ ፡ ኢዮአስ ፡ ዮዳሄ ፡ ያደረገለትን ፡ ቸርነት ፡ አላሰበም ፥ ልጁንም ፡ ዘካርያስን ፡ አስገደለው ፤ እርሱም ፡ ሲሞት ፡— እግዚአብሔር ፡ ይየው ፥ ይፈልገውም ፡ አለ ።

፳፫ ዓመቱም ፡ ካለፈ ፡ በኋላ ፡ የሶርያውያን ፡ ሠራዊት ፡ መጡበት ፤ ወደ ፡ ይሁዳና ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ መጥተው ፡ ከሕዝቡ ፡ መካከል ፡ የሕዝቡን ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ አጠፉ ፥ ምርኮአቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ ላኩ ። ፳፬ የሶርያውያንም ፡ ሠራዊት ፡ ቍጥር ፡ ጥቂት ፡ ሆኖ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ታላቅን ፡ ሠራዊት ፡ አሳልፎ ፡ በእጃቸው ፡ ሰጣቸው ፤ ይህም ፡ የሆነው ፡ የአባቶቻቸውን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትተው ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ነው ። እነርሱም ፡ በኢዮአስ ፡ ላይ ፡ ፍርድ ፡ ፈረዱበት ።

፳፭ ከእርሱም ፡ ዘንድ ፡ አልፈው ፡ ከሄዱ ፡ በኋላ ፡ እጅግ ፡ ታምሞ ፡ ነበር ፤ የገዛ ፡ ባሪያዎቹም ፡ ስለ ፡ ካህኑ ፡ ስለ ፡ ዮዳሄ ፡ ልጅ ፡ ተበቅለው ፡ ተማማሉበት ፥ በአልጋውም ፡ ላይ ፡ ገደሉት ፥ ሞተም ፤ በዳዊት ፡ ከተማ ፡ እንጂ ፡ በነገሥታት ፡ መቃብር ፡ አልቀበሩትም ። ፳፮ የተማማሉበትም ፡ የአሞናዊቱ ፡ የሰምዓት ፡ ልጅ ፡ ዛባድ ፥ የሞዓባዊቱም ፡ የሰማሪት ፡ ልጅ ፡ ዮዛባት ፡ ነበሩ ። ፳፯ የልጆቹና ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ የተደረገው ፡ ነገር ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ ማደሱ ፥ እነሆ ፥ በነገሥታቱ ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፎአል ። ልጁም ፡ አሜስያስ ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

፩ አሜስያስም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ሀያ ፡ ዘጠኝ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱ ፡ ዮዓዳን ፡ የተባለች ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ሴት ፡ ነበረች ። ፪ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አደረገ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ በፍጹም ፡ ልብ ፡ አይደለም ። ፫ መንግሥትም ፡ በጸናለት ፡ ጊዜ ፡ አባቱን ፡ የገደሉትን ፡ ባሪያዎች ፡ ገደለ ። ፬ በሙሴም ፡ ሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፥ እግዚአብሔርም ፡— ሰው ፡ ሁሉ ፡ በገዛ ፡ ኃጢአቱ ፡ ይሙት ፡ እንጂ ፡ አባቶች ፡ በልጆች ፡ ፋንታ ፡ አይሙቱ ፥ ልጆችም ፡ በአባቶች ፡ ፋንታ ፡ አይሙቱ ፡ ብሎ ፡ እንዳዘዘ ፡ የነፍሰ ፡

ገዳዮችን ፡ ልጆች ፡ አልገደለም ።

፭ አሜስያስም ፡ ይሁዳን ፡ ሰበሰበ ÷ በየአባቶቻቸውም ፡ ቤቶች ፡ ከሺህ ፡ አለቆችና ፡ ከመቶ ፡ አለቆች ፡ እጅ ፡ በታች ፡ አቆማቸው ፤ ከሀያ ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያሉትን ፡ ይሁዳንና ፡ ብንያምን ፡ ሁሉ ፡ ቈጠረ ÷ ለሰልፍም ፡ የሚወጡ ÷ ጋሻና ፡ ጦርም ፡ የሚይዙ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ የተመረጡ ፡ ሰዎች ፡ አገኘ ። ፮ ደግሞም ፡ ከእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላን ፡ በመቶ ፡ መክሊት ፡ ብር ፡ ቀጠረ ። ፯ አንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጥቶ ፦ ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ እግዚአብሔር ፡ ከእስራኤልና ፡ ከኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ አይደለምና ፡ የእስራኤል ፡ ጭፍራ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አይውጣ ። ፰ ብትሄድ ፡ ግን ÷ በእነርሱም ፡ ማሸነፍን ፡ ብታስብ ÷ የመርዳትና ፡ የመጣል ፡ ኃይል ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነውና ፡ እግዚአብሔር ፡ በጠላቶችህ ፡ ፊት ፡ ይጥልሃል ፡ አለው ። ፱ አሜስያስም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሰው ፦ ለእስራኤል ፡ ጭፍራ ፡ የሰጠሁት ፡ መቶ ፡ መክሊት ፡ ምን ፡ ይሁን ? አለው ። የእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፦ ከዚህ ፡ አብልጦ ፡ ይሰጥህ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይችላል ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ። ፲ አሜስያስም ፡ ከኤፍሬም ፡ የመጡት ፡ ጭፍሮች ፡ ወደ ፡ ስፍራቸው ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ ለይቶ ፡ አሰናበታቸው ፤ ስለዚህም ፡ ቍጣቸው ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ጸና ÷ ወደ ፡ አገራቸውም ፡ በጽኑ ፡ ቍጣ ፡ ተመለሱ ። ፲፩ አሜስያስም ፡ በረታ ÷ ሕዝቡንም ፡ አውጥቶ ፡ ወደ ፡ ጨው ፡ ሸለቆ ፡ ሄደ ÷ ከሴይርም ፡ ልጆች ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ገደለ ። ፲፪ የይሁዳም ፡ ልጆች ፡ ደግሞ ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ሰዎችን ፡ በሕይወታቸው ፡ ማረኩ ÷ ወደ ፡ ዓለቱም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ አመጡአቸው ፤ ከዓለቱም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ጣሉአቸው ÷ ሁሉም ፡ ተፈጠፈጡ ። ፲፫ አሜስያስ ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ እንዳይሄዱ ፡ ያሰናበታቸው ፡ ጭፍሮች ፡ ከሰማርያ ፡ ጀምረው ፡ እስከ ፡ ቤትሖሮን ፡ ድረስ ፡ በይሁዳ ፡ ከተሞች ፡ ላይ ፡ አደጋ ፡ ጣሉ ÷ ከእነርሱም ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ገደሉ ÷ ብዙ ፡ ምርኮም ፡ ማረኩ ።

፲፬ አሜስያስም ፡ የኤዶምያስን ፡ ሰዎች ፡ ከገደለ ፡ በኋላ ፡ የሴይርን ፡ ልጆች ፡ አማልክት ፡ አመጣ ÷ የእርሱም ፡ አማልክት ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ አቆማቸው ÷ ይሰግድላቸውም ፡ ያጥንላቸውም ፡ ነበር ። ፲፭ ስለዚህም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በአሜስያስ ፡ ላይ ፡ ነደደና ፦ ሕዝባቸውን ፡ ከአንተ ፡ እጅ ፡ ያላዳኑትን ፡ የአሕዛብን ፡ አማልክት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ፈለግሃቸው ? የሚል ፡ ነቢይ ፡ ሰደደበት ። ፲፮ እርሱም ፡ ሲናገር ፡ ንጉሡ ፦ በውኑ ፡ አንተ ፡ የንጉሡ ፡ አማካሪ ፡ ልትሆን ፡ ሾመንሃልን ? ተው ፤ ቅጣትን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትሻለህ ? አለው ። ነቢዩም ፦ ይህን ፡ አድርገሃልና ÷ ምክሬንም ፡ አልሰማህምና ፡ እግዚአብሔር ፡ ሊያጠፋህ ፡ እንዳሰበ ፡ አወቅሁ ፡ ብሎ ፡ ተወ ።

፲፯ የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ አሜስያስ ፡ ምክር ፡ አደረገና ፦ ና ÷ እርስ ፡ በርሳችን ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ እንተያይ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ኢዩ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢዮአካዝ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢዮአስ ፡ ላከ ። ፲፰ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮአስ ፦ የሊባኖስ ፡ ኵርንችት ፦ ልጅህን ፡ ለልጄ ፡ ሚስት ፡ አድርገህ ፡ ስጠው ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ሊባኖስ ፡ ዝግባ ፡ ላከ ፤ የሊባኖስም ፡ አውሬ ፡ አልፎ ፡ ኵርንችቱን ፡ ረገጠ ። ፲፱ አንተም ፦ እነሆ ÷ ኤዶምያስን ፡ መትቻለሁ ፡ ብለህ ፡ ኰርተሃል ፤ በቤትህ ፡ ተቀመጥ ፤ አንተ ፡ ከይሁዳ ፡ ጋር ፡ ትወድቅ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ መከራ ፡ ትሻለህ ? ብሎ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ አሜስያስ ፡ ላከ ።

፳ የኤዶምያስንም ፡ አማልክት ፡ ስለ ፡ ፈለጉ ፡ በጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ነበረና ፡ አሜስያስ ፡ አልሰማም ። ፳፩ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮአስ ፡ ወጣ ፤ እርሱና ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ አሜስያስም ፡ በይሁዳ ፡ ባለች ፡ በቤትሳሚስ ፡ ላይ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተያዩ ። ፳፪ ይሁዳም ፡ በእስራኤል ፡ ፊት ፡ ተመታ ÷ እያንዳንዱም ፡ ወደ ፡ ድንኳኑ ፡ ሸሸ ። ፳፫ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮአስ ፡ የይሁዳን ፡ ንጉሥ ፡ የአካዝያስን ፡ ልጅ ፡ የኢዮአስን ፡ ልጅ ፡ አሜስያስን ፡ በቤትሳሚስ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ አመጣው ÷ የኢየሩሳሌምንም ፡ ቅጥር ፡ ከኤፍሬም ፡ በር ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ማዕዘኑ ፡ በር ፡ ድረስ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ አፈረሰ ። ፳፬ ወርቁንና ፡ ብሩን ፡ ሁሉ ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ከዖቤድኤዶም ፡ ጋር ፡ የነበሩትን ፡ ዕቃዎች ፡ ሁሉ ÷ የንጉሡንም ፡ ቤት ፡ መዛግብት ÷ በመያዣ ፡ የተያዙትንም ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ ሰማርያ ፡ ተመለሰ ።

፳፭ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ የኢዮአስ ፡ ልጅ ፡ አሜስያስ ፡ ከእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ከኢዮአካዝ ፡ ልጅ ፡ ከኢዮአስ ፡ ሞት ፡ በኋላ ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ኖረ ። ፳፮ የቀረውም ፡ የፊተኛውና ፡ የኋለኛው ፡ የአሜስያስ ፡ ነገር ÷ እነሆ ÷ በይሁዳና ፡ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ፳፯ አሜስያስም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከመከተል ፡ ከራቀ ፡ በኋላ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የዓመፅ ፡ መሐላ ፡ አደረጉበት ÷ ወደ ፡ ለኪሶም ፡ ኰበለለ ፤ በስተ ፡ ኋላውም ፡ ወደ ፡ ለኪሶ ፡ ላኩ ÷ በዚያም ፡ ገደሉት ። ፳፰ በፈረስም ፡ ጭነው ፡ አመጡት ÷ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ቀበሩት ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩ የይሁዳም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ የአሥራ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ የነበረውን ፡ ዖዝያንን ፡ ወስደው ፡ በአባቱ ፡ በአሜስያስ ፡ ፋንታ ፡ አነገሡት ። ፪ ንጉሡም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ ከአንቀላፋ ፡ በኋላ ፡ ዖዝያን ፡ ኤላትን ፡ ሠራ ÷ ወደ ፡ ይሁዳም ፡ መለሳት ። ፫ ዖዝያንም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የአሥራ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ÷ በኢየሩሳሌምም ፡ አምሳ ፡

ሁለት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡ ይከልያ ፡
የተባለች ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ሴት ፡ ነበረች ።
፬ ፡ አባቱም ፡ አሜስያስ ፡ እንዳደረገው ፡ ሁሉ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አደረገ ።
፭ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ መፍራት ፡ በስተማረ ፡ በዘ
ካርያስ ፡ ዘመን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይፈልግ ፡
ዘንድ ፡ ልብ ፡ አደረገ ፤ እግዚአብሔርንም ፡ በፈ
ለገ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነገሩን ፡ አከናወነለት ።
፮ ፡ ወጥቶም ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ ጋር ፡ ተዋጋ ፥
የጌትንና ፡ የየብናን ፡ የአዛጦንንም ፡ ቅጥር ፡
አፈረሰ ፤ በአዛጦንና ፡ በፍልስጥኤማውያንም ፡
፯ ፡ አገር ፡ ከተሞችን ፡ ሠራ ። እግዚአብሔርም ፡
በፍልስጥኤማውያንና ፡ በጉርበኣል ፡ በሚኖሩ ፡
ዓረባውያን ፡ በምዑናውያንም ፡ ላይ ፡ ረዳው ።
፰ ፡ አሞናውያንም ፡ ለዖዝያን ፡ ገበሩ ፤ እጅግም ፡
በርትቶ ፡ ነበርና ፡ ዝናው ፡ እስከ ፡ ግብጽ ፡ መግ
፱ ፡ ቢያ ፡ ድረስ ፡ ተሰማ ። ዖዝያንም ፡ በኢየሩሳሌም ፡
በማዕዘኑ ፡ በርና ፡ በሸለቆው ፡ በር ፡ ቅጥሩም ፡
በዞረበት ፡ ማዕዘን ፡ አጠገብ ፡ ግንቦችን ፡ ሠርቶ ፡
፲ ፡ መሸጋቸው ። ብዙም ፡ እንስሶች ፡ ነበሩትና ፡
በምድረ ፡ በዳውና ፡ በቈላው ፡ በደጋውም ፡
ግንብ ፡ ሠራ ፥ ብዙ ፡ ጕድጓድም ፡ ማሰ ፤ ደግ
ሞም ፡ እርሻ ፡ ይወድድ ፡ ነበርና ፡ በተራራማ
ውና ፡ በፍሬያማው ፡ስፍራ ፡ አራሾችና ፡ አት
፲፩ ፡ ክልተኞች ፡ ነበሩት ። ደግሞም ፡ ለዖዝያን ፡
በሠራዊት ፡ ውስጥ ፡ ሰልፈኞች ፡ ነበሩት ፤ በን
ጉሡ ፡ አለቃ ፡ በሐናንያ ፡ ትእዛዝ ፡ በአለቃው ፡
በመዕሤያና ፡ በጸሐፊው ፡ በይዒኤል ፡ እጅ ፡
እንደ ፡ ተቈጠሩ ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ በየቍጥራቸው ፡
፲፪ ፡ ይወጡ ፡ ነበር ። የአባቶቻቸውም ፡ ቤቶች ፡
አለቆች ፡ የጽኑዓን ፡ ኃያላኑ ፡ ቍጥር ፡ ሁሉ ፡
፲፫ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ነበረ ። ንጉሡ
ንም ፡ በጠላቱ ፡ ላይ ፡ ያግዝ ፡ ዘንድ ፥ በታላቅ ፡
ኃይል ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚወጣ ፥ ከእጃቸው ፡
በታች ፡ የነበረ ፡ ሠራዊት ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሰባት ፡
፲፬ ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ነበረ ። ዖዝያንም ፡ ለጭ
ፍራው ፡ ሁሉ ፡ ጋሻና ፡ ጦር ፥ ራስ ፡ ቍርና ፡
ጥሩር ፥ ቀስትና ፡ የሚወነጭፉትን ፡ ድንጋይ ፡ አዘ
፲፭ ፡ ጋጀላቸው ። በኢየሩሳሌምም ፡ በብልሃተኞች ፡
እጅ ፡ የተሠሩትን ፥ በግንብና ፡ በቅጥር ፡ ላይ ፡
የሚኖሩትን ፥ ፍላጻና ፡ መርግ ፡ የሚወረወርባ
ቸውን ፡ መሣሪያዎች ፡ አደረገ ፤ እስኪበረታም ፡
ድረስ ፡ እግዚአብሔር ፡ በድንቅ ፡ ረድቶታልና ፡
ዝናው ፡ እስከ ፡ ሩቅ ፡ ድረስ ፡ ተሰማ ።
፲፮ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ በበረታ ፡ ጊዜ ፡ ለጥፋት ፡ ልቡ ፡
ታበየ ፥ አምላኩንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ በደለ ፤
ወደ ፡ መቅደስ ፡ ገብቶ ፡ በዕጣን ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡
፲፯ ፡ ዕጠነ ። ካህኑም ፡ ዓዛርያስ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡
ጽኑዓን ፡ የነበሩ ፡ ሰማንያ ፡ የእግዚአብሔር ፡
፲፰ ፡ ካህናት ፡ ተከትለው ፡ ገቡ ። ንጉሡንም ፡ ዖዝ
ያንን ፡ እየተቃወሙ ፡— ዖዝያን ፡ ሆይ ፥ ዕጣን ፡
ማጠን ፡ የተቀደሱት ፡ የአሮን ፡ ልጆች ፡ የካህ
ናቱ ፡ ሹመት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ታጥን ፡ ዘንድ ፡ ለአንተ ፡ አይገባህም ፤ በድለሃ
ልና ፡ ከመቅደሱ ፡ ውጣ ፤ ከአምላክም ፡ ከእግ
ዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ክብር ፡ አይሆንልህም ፡
፲፱ ፡ አሉት ። ዖዝያንም ፡ ተቈጣ ፤ የሚያጥንበትም ፡
ጥና ፡ በእጁ ፡ ነበረ ፤ ካህናቱንም ፡ በተቈጣ ፡
ጊዜ ፡ በካህናቱ ፡ ፊት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
ውስጥ ፡ በዕጣኑ ፡ መሠዊያ ፡ አጠገብ ፡ ሳለ ፡ በግ
፳ ፡ ምባሩ ፡ ላይ ፡ ለምጽ ፡ታየ ። ታላቁም ፡ ካህን ፡
ዓዛርያስ ፡ ካህናቱም ፡ ሁሉ ፡ ተመለከቱት ፥ እነ
ሆም ፥ በግምባሩ ፡ ላይ ፡ ለምጽ ፡ ነበረ ፤ ፈጥነ
ውም ፡ አባረሩት ፥ እርሱም ፡ ደግሞ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ቀሥፎት ፡ ነበርና ፡ ይወጣ ፡ ዘንድ ፡
፳፩ ፡ ቸኰለ ። ንጉሡም ፡ ዖዝያን ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡
ለምጻም ፡ ነበረ ፤ ለምጻምም ፡ ሆኖ ፡ ከእግዚአ
ብሔር ፡ ቤት ፡ ተቈርጦአልና ፡ በተለየ ፡ ቤት ፡
ይቀመጥ ፡ ነበር ፤ ልጁም ፡ ኢዮአታም ፡ በን
ጉሡ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ በምድሩ ፡ ሕዝብ ፡
፳፪ ፡ ላይ ፡ ይፈርድ ፡ ነበር ። የቀረውንም ፡ የፊተኛ
ውንና ፡ የኋለኛውን ፡ የዖዝያንን ፡ ነገር ፡ ነቢዩ ፡
፳፫ ፡ የአሞጽ ፡ ልጅ ፡ ኢሳይያስ ፡ጽፎታል ። ዖዝያ
ንም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ ለምጻም ፡
ነው ፡ ብለውም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ በነገሥታቱ ፡
መቃብር ፡ እርሻ ፡ ውስጥ ፡ ቀበሩት ፤ ልጁም ፡
ኢዮአታም ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

፩ ፡ ኢዮአታምም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡
የሀያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢ
የሩሳሌምም ፡ አሥራ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤
እናቱም ፡ የሳዶቅ ፡ ልጅ ፡ ኢየሩሳ ፡ ትባል ፡
፪ ፡ ነበር ። አባቱም ፡ ዖዝያን ፡ እንዳደረገ ፡ ሁሉ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አደረገ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ አል
፫ ፡ ገባም ፤ ሕዝቡም ፡ ገና ፡ ይበድል ፡ ነበር ። የእ
ግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ የላይኛውን ፡ በር ፡ ሠራ ፥
፬ ፡ በዖፌልም ፡ ቅጥር ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡ ሠራ ። በተ
ራራማውም ፡ በይሁዳ ፡ አገር ፡ ላይ ፡ ከተሞችን ፡
ሠራ ፥ በዱር ፡ ስፍራዎችም ፡ አምባዎችንና ፡
፭ ፡ ግንቦችን ፡ ሠራ ። ከአሞንም ፡ ልጆች ፡ ንጉሥ ፡
ጋር ፡ ተዋጋ ፡ አሸነፋቸውም ። በዚያም ፡ ዓመት ፡
የአሞን ፡ ልጆች ፡ መቶ ፡ መክሊት ፡ ብር ፥
አሥር ፡ ሺህም ፡ የቆሬስ ፡ መስፈሪያ ፡ስንዴ ፥
አሥር ፡ ሺህም ፡ የቆሬስ ፡ መስፈሪያ ፡ ገብስ ፡
ሰጡት ። እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ የአሞን ፡ ልጆች ፡
በሁለተኛውና ፡ በሦስተኛው ፡ ዓመት ፡ ሰጡት ።
፮ ፡ ኢዮአታምም ፡ በአምላኩ ፡ በእግዚአብሔር ፡
፯ ፡ ፊት ፡ መንገዱን ፡ አቅንቶአልና ፡ በረታ ። የቀ
ረውም ፡ የኢዮአታም ፡ ነገር ፥ ሰልፉም ፡ ሁሉ ፥
ሥራውም ፥ እነሆ ፥ በእስራኤልና ፡ በይሁዳ ፡ ነገ
፰ ፡ ሥታት ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፎአል ። መንገሥ ፡
በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ጕል
ማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ አሥራ ፡ ስድ
፱ ፡ ስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። ኢዮአታምም ፡ ከአባ
ቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ቀበ
ሩት ፤ ልጁም ፡ አካዝ ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፳፰ ።

፩፤ አካዝ ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ፡
ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ÷ በኢየሩሳሌምም ፡
አሥራ፡ስድስት፡ዓመት፡ነገሠ፤እንደ፡አባቱም፡
እንደ፡ዳዊት፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡ቅን፡ነገር፡
፪፤ አላደረገም ። ነገር ፡ ግን ፡ በእስራኤል ፡ ነገሥ
ታት፡መንገድ፡ሄደ÷ደግሞም፡ለበኣሊም፡ቀል
፫፤ ጠው፡የተሠሩትን፡ምስሎችን፡ሠራ ። ደግ
ሞም፡ በሄኖም፡ ልጅ፡ ሸለቆ፡ ውስጥ፡ ዐጠነ፤
እግዚአብሔር ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡
እንዳሳደዳቸው፡እንደ፡አሕዛብም፡ክፉ፡ልማድ፡
፬፤ ልጆቹን ፡ በእሳት ፡ አቃጠለ ። በኰረብታው ፡
መስገጃዎችና ፡ በተራሮች ፡ ላይ ፡ በለመለመ
ውም ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ በታች ፡ ይሠዋና ፡ ያጥን ፡
ነበር ።

፭፤ ስለዚህ፡አምላኩ፡እግዚአብሔር፡በሶርያ፡
ንጉሥ ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠው ፤ ሶርያውያ
ንም ፡ መቱት ÷ ከእርሱም ፡ ብዙ ፡ ምርኮኞች ፡
ወሰደው ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ አመጡ ። ደግሞም፡
በእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠው ፤
፮፤ እርሱም ፡ በታላቅ ፡ አመታት ፡ መታው ። የአ
ባቶቻቸውንም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡
ትተው ፡ ነበርና ፡ የሮሜልዩ ፡ ልጅ ፡ ፋቁሔ ፡
በአንድ ፡ ቀን ፡ ከይሁዳ ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሺህ ፡
፯፤ ገደለ ፤ ሁሉም ፡ ጽኑዓን ፡ ነበሩ ። ከኤፍሬም ፡
ወገን ፡ የነበረው ፡ ኃያል ፡ ሰው ፡ ዝክሪ ፡ የንጉ
ሡን ፡ ልጅ ፡ መዕሤያንና ፡ የቤቱን ፡ አዛዥ ፡ ዓዝ
ሪቃምን ÷ ለንጉሡም ፡ በማዕርግ ፡ ሁለተኛ ፡
የሆነውን ፡ ሕልቃናን ፡ ገደለ ።

፰፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከወንድሞቻቸው ፡
ሁለት ፡ መቶ ፡ ሺህ ፡ ሴቶችን ÷ ወንዶችና ፡
ሴቶች ፡ ልጆችንም ፡ ማረኩ ÷ እጅግም ፡ ምርኮ ፡
፱፤ ከእነርሱ ፡ ወሰደው ፡ ወደ ፡ ሰማርያ ፡ አገቡ ። በዚ
ያም ፡ ዖዴድ ፡ የተባለ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነቢይ ፡
ነበረ ፤ ወደ ፡ ሰማርያም ፡ የሚመጣውን ፡ ጭፍራ ፡
ሊገናኘው ፡ ወጣ ÷ እንዲህም ፡ አላቸው ፦
እነሆ ÷ የአባቶቻችሁ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡
ይሁዳን ፡ ስለ ፡ ተቈጣ ፡ በእጃችሁ ፡ አሳልፎ ፡
ሰጣቸው ÷ እናንተም ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ በሚደ
፲፤ ርስ ፡ ቍጣ ፡ ገደላችኋቸው ። አሁንም ፡ የይ
ሁዳና ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ልጆች ፡ በሪያዎች ፡
ሆነው ፡ ይገዙላችሁ ፡ ዘንድ ፡ ታስባላችሁ ፤ ነገር ፡
ግን ፡ አምላካችሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ የበደላ
ችሁት ፡ በደል ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ የለምን ?
፲፩፤ አሁንም ፡ ስሙኝ ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡
በላያችሁ ፡ ነድዶአልና ፡ ከወንድሞቻችሁ ፡ የወ
፲፪፤ ሰዳችኋቸውን ፡ ምርኮኞች ፡ መልሱ ። ደግ
ሞም ፡ ከኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ አለቆች ፡ የዮሐ
ናን ፡ ልጅ ፡ ዓዛርያስ ÷ የምሺሌሞትም ፡ ልጅ ፡
በራክያ ÷ የሰሎምም ፡ ልጅ ፡ ይሒዝቅያ ÷ የሐ
ድላይም ፡ ልጅ ፡ ዓሜሳይ ፡ ከሰልፍ ፡ በተመ
፲፫፤ ለሱት ፡ ላይ ፡ ተቃወሙአቸው ። ደግሞም ፦
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ በደል ፡
ታመጡብናላችሁና ÷ ኃጢአታችንንና ፡ በደላ
ላችንን ፡ ታበዙብናላችሁና ፡ የተማረኩትን ፡
ወደዚህ ፡ አታግቡ ፤ በደላችን ፡ ታላቅ ፡ ነውና ÷
የመቅሠፍቱም ፡ ቍጣ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡
፲፬፤ ነውና ፡ አሉአቸው ። ሰልፈኞቹም ፡ ምርኮኞ
ቹንና ፡ ምርኮውን ፡ በአለቆችና ፡ በጉባኤ ፡ ሁሉ ፡
፲፭፤ ፊት ፡ ተዉ ። በስማቸውም ፡ የተጻፉ ፡ ሰዎች ፡
ተነሥተው ፡ ምርኮኞቹን ፡ ወሰዱ ÷ በመካከላ
ቸውም ፡ ራቁታቸውን ፡ ለነበሩት ፡ ሁሉ ፡ ከም
ርኮው ፡ አለበሱአቸው ÷ አጐናጸፉአቸውም ÷
ጫማም ፡ በእግራቸው ፡ አደረጉላቸው ÷ መገቡ
አቸውም ÷ አጠጡአቸውም ÷ ቀቡአቸውም ፤
ደካሞቹንም ፡ ሁሉ ፡ በአህዮች ፡ ላይ ፡ አስቀመ
ጡአቸው ÷ ዘንባባም ፡ ወዳለበት ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡
ኢያሪኮ ፡ ወደ ፡ ወንድሞቻቸው ፡ አመጡአ
ቸው ፤ ወደ ፡ ሰማርያም ፡ ተመለሱ ።

፲፮፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ንጉሡ ፡ አካዝ ፡ እርዳታ ፡
፲፯፤ ፈልጎ ፡ ወደ ፡ አሦር ፡ ንጉሥ ፡ ላከ ፤ የኤዶም
ያስ ፡ ሰዎች ፡ ዳግመኛ ፡ መጥተው ÷ ይሁዳንም ፡
መትተው ፡ ብዙ ፡ ምርኮኛ ፡ ወስደው ፡ ነበርና ።
፲፰፤ ደግሞም ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ በቈላውና ፡ በደ
ቡብ ፡ በኩል ፡ ባሉት ፡ በይሁዳ ፡ ከተሞች ፡
አደጋ ፡ ጥለው ፡ ነበር ፤ ቤትሳሚስንና ፡ ኤሎንን ÷
ግዴሮትንም ÷ ሦኮንና ፡ መንደሮችዋን ÷ ተም
ናንና ፡ መንደሮችዋን ÷ ጊምዞንና ፡ መንደሮች
ዋን ፡ ወስደው ፡ በዚያ ፡ ተቀምጠው ፡ ነበር ።
፲፱፤ የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ አካዝ ፡ እግዚአብሔርን ፡
ክዶአልና ÷ ከእርሱም ፡ እጅግ ፡ ርቆአልና ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ይሁዳን ፡ አዋረደው ።
፳፤ የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ ቴልጌልቴልፌልሶር ፡
መጥቶ ፡ አስጨነቀው ፡ እንጂ ፡ አልረዳውም ።
፳፩፤ አካዝም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ከንጉሡና ፡
ከአለቆቹም ፡ ቤት ፡ እዥሌታውን ፡ ገፈፈ ÷ ለአ
ሦርም ፡ ንጉሥ ፡ ሰጠ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አንዳች ፡
አልተጠቀመበትም ።

፳፪፤ ይህም ፡ ንጉሥ ፡ አካዝ ፡ በተጨነቀ ፡ ጊዜ ፡
፳፫፤ እግዚአብሔርን ፡ መበደል ፡ አበዛ ። ለመቱ
ትም ፡ ለደማስቆ ፡ አማልክት ፦ የሶርያን ፡ ነገ
ሥታት ፡ አማልክት ፡ ረድተዋቸዋልና ፡ እኔን ፡
ይረዱ ፡ ዘንድ ፡ እሠዋላቸዋለሁ ፡ ብሎ ፡ ሠዋላ
ቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ ለእርሱና ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡
፳፬፤ ዕንቅፋት ፡ ሆኑ ። አካዝም ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ቤት ፡ ዕቃዎች ፡ ሁሉ ፡ ወስዶ ፡ ሰባበራቸው ÷
የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ ደጅ ፡ ቈለፈ ፤ በኢ
የሩሳሌምም ፡ ማዕዘን ፡ ሁሉ ፡ መሠዊያ ፡ ሠራ ።
፳፭፤ በይሁዳም ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ለሌሎች ፡ አማል
ክት ፡ ያጥን ፡ ዘንድ ፡ የኰርብታ ፡ መስገጃዎች ፡
አሠራ ፤ የአባቶቹንም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔ
፳፮፤ ርን ፡ አስቈጣ ። የቀረውም ፡ ነገርና ፡ ሥራው ፡
ሁሉ ÷ የፊተኛውና ፡ የኋለኛው ÷ እነሆ ÷ በይ
ሁዳና ፡ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ መጽሐፍ ፡
፳፯፤ ተጽፎአል ። አካዝም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀ
ላፋ ÷ በከተማይቱም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ቀበሩት ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ መቃ

ብር ፡ አላገቡትም ፤ ልጁም ፡ ሕዝቅያስ ፡ በእርሱ ፡
ፋንታ ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

፩ ሕዝቅያስም ፡ የሀያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ጕል
ማሳ ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፡ መንገሥ ፡ ጀመረ ፥ በኢየ
ሩሳሌም ፡ ሀያ ፡ ዘጠኝ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እናቱም ፡
፪ የዘካርያስ ፡ ልጅ ፡ አቡ ፡ ትባል ፡ ነበር ። አባ
ቱም ፡ ዳዊት ፡ እንዳደረገ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብ
፫ ሔር ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አደረገ ። በነገሠም ፡
በመጀመሪያው ፡ ዓመት ፡ በመጀመሪያው ፡ ወር ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ደጆች ፡ ከፈተ ፥ አደ
፬ ሳቸውም ። ካህናቱንና ፡ ሌዋውያኑንም ፡ አስ
መጣ ፥ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ባለው ፡ አደባባ
፭ ይም ፡ ሰበሰባቸው ፥ እንዲህም ፡ አላቸው ፡—
ሌዋውያን ፡ ሆይ ፥ ስሙኝ ፤ ተቀደሱ ፥ የአባቶ
ቻችሁንም ፡ አምላክ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡
ቀድሱ ፤ ርኩስን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ከመቅደሱ ፡ አስ
፮ ወግዱ ። አባቶቻችን ፡ ተላልፈዋል ፥ በአምላ
ካችንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አድር
ገዋል ፤ እርሱንም ፡ ትተዋል ፥ ፊታቸውንም ፡
ከእግዚአብሔር ፡ መኖሪያ ፡ መልሰዋል ፥ ወደ ፡
፯ እርስዋም ፡ ጀርባቸውን ፡ አዙረዋል ፤ ደግሞም ፡
የወለሉን ፡ ደጆች ፡ ቈልፈዋል ፥ መብራቶቹ
ንም ፡ አጥፍተዋል ፥ በመቅደሱም ፡ ውስጥ ፡
ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ አላጠኑም ፥ የሚቃጠለ
፰ ውንም ፡ መሥዋዕት ፡ አላቀረቡም ። ስለዚህም ፡
የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩ
ሳሌም ፡ ላይ ፡ ሆነ ፥ በዓይናችሁም ፡ እንደም
ታዩ ፡ ለድንጋጤና ፡ ለመደነቂያ ፡ ለመዘበቻም ፡
፱ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ። እነሆም ፥ ስለዚህ ፡ አባ
ቶቻችን ፡ በሰይፍ ፡ ወደቁ ፥ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡
፲ ልጆቻችንም ፡ ሚስቶቻችንም ፡ ተማረኩ ። አሁ
ንም ፡ የቍጣው ፡ ጽናት ፡ ከእኛ ፡ እንዲመለስ ፡
ከእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡
ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ በልቤ ፡ አስቤአ
፲፩ ለሁ ። ልጆቼ ፡ ሆይ ፥ በፊቱ ፡ ትቆሙና ፡ ታገለ
ግሉት ፡ ዘንድ ፥ አገልጋዮቹም ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ፥
ታጥኑለትም ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ መርጦ
አችኋልና ፡ ቸል ፡ አትበሉ ።

፲፪ ሌዋውያኑም ፥ ከቀዓት ፡ ልጆች ፡ የአማሢ ፡
ልጅ ፡ መሐትና ፡ የዓዛርያስ ፡ ልጅ ፡ ኢዮኤል ፥
ከሜራሪም ፡ ልጆች ፡ የአብዲ ፡ ልጅ ፡ ቂስና ፡
የይሃሌልኤል ፡ ልጅ ፡ ዓዛርያስ ፥ ከጌድሶንም ፡
ልጆች ፡ የዛማት ፡ ልጅ ፡ ዮአክና ፡ የዮአክ ፡ ልጅ ፡
፲፫ ፲፬ ዔድን ፥ ከኤሊጻፋንም ፡ ልጆች ፡ ሺምሪና ፡ ይዒ
ኤል ፥ ከአሳፍም ፡ ልጆች ፡ ዘካርያስና ፡ መታንያ ፥
ከኤማንም ፡ ልጆች ፡ ይሒኤልና ፡ ሰሚኢ ፥ ከኤ
ዶታምም ፡ ልጆች ፡ ሸማያና ፡ ዑዝኤል ፡ ተነሡ ።
፲፭ ወንድሞቻቸውንም ፡ ሰብስበው ፡ ተቀደሱ ፤ በእ
ግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንደ ፡ መጣው ፡ እንደ ፡
ንጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ያነጹ ፡
፲፮ ዘንድ ፡ ገቡ ። ካህናቱም ፡ ያነጹት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ውስጡ ፡ ገቡ ፥
በእግዚአብሔርም ፡ መቅደስ ፡ ያገኙትን ፡ ርኩስ ፡
ነገር ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አደ
ባባይ ፡ አወጡት ። ሌዋውያንም ፡ ወስደው ፡
ወደ ፡ ሜዳ ፡ ወደ ፡ ቄድሮን ፡ ወንዝ ፡ ጣሉት ።
፲፯ በመጀመሪያውም ፡ ወር ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡
ይቀድሱ ፡ ጀመር ፥ በዚያውም ፡ ወር ፡ በስምን
ተኛው ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
ወለል ፡ ደረሱ ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡
በስምንት ፡ ቀን ፡ ቀደሱ ፥ በመጀመሪያውም ፡
ወር ፡ በአሥራ ፡ ስድስተኛው ፡ ቀን ፡ ፈጸሙ ።
፲፰ ወደ ፡ ውስጡም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ሕዝቅ
ያስ ፡ ገብተው ፡— የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡
ሁሉ ፥ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆነውን ፡
መሠዊያና ፡ ዕቃውንም ፡ ሁሉ ፥ የገጹንም ፡ ኅብ
ስት ፡ ገበታና ፡ ዕቃውን ፡ ሁሉ ፡ አንጽተናል ፤
፲፱ ንጉሡም ፡ አካዝ ፡ ነግሦ ፡ ሳለ ፡ በመተላለፍ ፡
ያረከሰውን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ አዘጋጅተናል ፡ ቀድ
ሰናልም ፤ እነሆም ፥ በእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡
ፊት ፡ ሆነዋል ፡ አሉት ።

፳ ንጉሡም ፡ ሕዝቅያስ ፡ ማልዶ ፡ ተነሣ ፡ የከተ
ማይቱንም ፡ አለቆች ፡ ሰበሰበ ፥ ወደ ፡ እግዚአ
፳፩ ብሔርም ፡ ቤት ፡ ወጣ ። ስለ ፡ መንግሥቱና ፡ ስለ ፡
መቅደሱም ፡ ስለ ፡ ይሁዳም ፡ ሰባት ፡ ወይፈኖች ፥
ሰባትም ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ ሰባትም ፡ የበግ ፡ ጠቦ
ቶች ፥ ሰባትም ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፡ ለኃጢአት ፡
መሥዋዕት ፡ አመጡ ። የአሮንንም ፡ ልጆች ፡ ካህ
ናቱን ፡— በእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ አሳ
፳፪ ርጉአቸው ፡ አላቸው ። ወይፈኖቹንም ፡ አረዱ ፥
ካህናቱም ፡ ደሙን ፡ ተቀብለው ፡ በመሠዊያው ፡
ላይ ፡ ረጩት ፤ አውራ ፡ በጎቹንም ፡ አረዱ ፥ ደሙ
ንም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ረጩት ፤ ጠቦቶቹ
ንም ፡ አረዱ ፡ ደሙንም ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡
፳፫ ረጩት ። የኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆኑ
ትን ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፡ በንጉሡና ፡ በጉባኤው ፡
ፊት ፡ አቀረቡ ፥ እጃቸውንም ፡ ጫኑባቸው ፥
፳፬ ካህናቱም ፡ አረዱአቸው ፤ ንጉሡም ፡ የሚቃ
ጠል ፡ መሥዋዕትና ፡ የኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡
ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ እንዲደረግ ፡ አዝዞ ፡ ነበ
ርና ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ማስተስረያ ፡ ያደርጉ ፡
ዘንድ ፡ የኃጢአቱን ፡ መሥዋዕት ፡ ደም ፡ በመ
ሠዊያው ፡ ላይ ፡ አቀረቡ ።

፳፭ ይህንም ፡ ትእዛዝ ፡ እግዚአብሔር ፡ በነቢ
ያቱ ፡ እጅ ፡ አዝዞአልና ፡ እንደ ፡ ዳዊትና ፡ እንደ ፡
ንጉሡ ፡ ባለ ፡ ራእይ ፡ እንደ ፡ ጋድ ፥ እንደ ፡
ነቢዩም ፡ እንደ ፡ ናታን ፡ ትእዛዝ ፥ ጸናጽልና ፡
በገና ፡ መሰንቆም ፡ አስይዞ ፡ ሌዋውያንን ፡ በእ
፳፮ ግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አቆመ ። ሌዋውያንም ፡
የዳዊትን ፡ የዜማ ፡ ዕቃ ፡ ይዘው ፥ ካህናቱም ፡
፳፯ መለከቱን ፡ ይዘው ፡ ቆመው ፡ ነበር ። ሕዝቅያ
ስም ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ በመሠዊያ ፡
ላይ ፡ ያሳርጉ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ የሚቃጠለውም ፡
መሥዋዕት ፡ ማረግ ፡ በተጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የእግዚ
አብሔር ፡ መዝሙር ፡ ደግሞ ፡ ተጀመረ ፥ መለከ
ቱም ፡ ተነፋ ፥ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ የዳዊት ፡

፳፰ ዜማ ፡ ዕቃ ፡ ተመታ ። ጉባኤውም ፡ ሁሉ ፡ ሰገዱ ፥ መዘምራኑም ፡ ዘመሩ ፥ መለከተኞችም ፡ ነፉ ፤ የሚቃጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ሆነ ። ፳፱ ማቅረቡንም ፡ በፈጸሙ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሡና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩ ፡ ሁሉ ፡ አጐነበሱ ፡ ሰገዱም ። ፴ ንጉሡም ፡ ሕዝቅያስና ፡ አለቆቹ ፡ ሌዋውያንን ፡ በዳዊትና ፡ በባለ ፡ ራእዩ ፡ በአሳፍ ፡ ቃል ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ፡ አዘዙ ። በደስታም ፡ አመሰገኑ ፥ አጐነበሱም ፡ ሰገዱም ።

፴፩ ሕዝቅያስም ፡— አሁን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተቀድሳችኋል ፤ ቅረቡ ፥ መሥዋዕቱንና ፡ የምስጋናውን ፡ መሥዋዕት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አምጡ ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ። ጉባኤውም ፡ መሥዋዕቱንና ፡ የምስጋናውን ፡ መሥዋዕት ፡ አመጡ ፤ ልባቸውም ፡ የፈቀደ ፡ ሁሉ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ አመጡ ። ፴፪ ጉባኤውም ፡ ያመጡት ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ቍጥር ፡ ሰባ ፡ ወይፈን ፥ መቶም ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ ሁለት ፡ መቶም ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነበረ ፤ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ነበረ ። ፴፫ የተቀደሱትም ፡ ቍጥር ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ በሬዎች ፡ ሦስት ፡ ሺህም ፡ በጎች ፡ ነበረ ። ፴፬ ነገር ፡ ግን ፡ ካህናቱ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ለመገፈፍ ፡ ጥቂቶች ፡ ነበሩ ፤ ስለዚህም ፡ ሌዋውያን ፡ በቅን ፡ ልብ ፡ ከካህናት ፡ ይልቅ ፡ ይቀደሱ ፡ ነበርና ፡ ሥራው ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፥ ካህናቱም ፡ እስኪቀደሱ ፡ ድረስ ፡ ወንድሞቻቸው ፡ ሌዋውያን ፡ ያግዙአቸው ፡ ነበር ። ፴፭ የሚቃጠለውም ፡ መሥዋዕት ፡ የደኅንነቱም ፡ መሥዋዕት ፡ ስብ ፥ ከሚቃጠለውም ፡ መሥዋዕት ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ የሚቀርበው ፡ የመጠጥ ፡ ቍርባን ፥ ብዙ ፡ ነበረ ። እንዲሁም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አገልግሎት ፡ ተዘጋጀ ። ፴፮ ሕዝቅያስና ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ፡ ስላዘጋጀው ፡ ነገር ፡ ደስ ፡ አላቸው ። ይህም ፡ ነገር ፡ በድንገት ፡ ተደረገ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

፩ ለእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ፋሲካ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እንዲመጡ ፡ ሕዝቅያስ ፡ ወደ ፡ እስራኤልና ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ ላከ ፥ ደግሞም ፡ ወደ ፡ ኤፍሬምና ፡ ወደ ፡ ምናሴ ፡ ደብዳቤ ፡ ጻፈ ። ፪፣፫ ካህናቱም ፡ በሚበቃ ፡ ቍጥር ፡ ስላልተቀደሱ ፥ ሕዝቡም ፡ ገና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ስላልተሰበሰበ ፡ በጊዜው ፡ ያደርጉት ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉምና ፡ ንጉሡና ፡ አለቆቹ ፡ የኢየሩሳሌምም ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ በሁለተኛው ፡ ወር ፡ ፋሲካውን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ተመካከረው ፡ ነበር ። ፬ ነገሩም ፡ ለንጉሡና ፡ ለጉባኤው ፡ ሁሉ ፡ ዓይን ፡ መልካም ፡ ነበረ ። ፭ እንደ ፡ ተጻፈም ፡ በብዙ ፡ ቍጥር ፡ አላደረጉትም ፡ ነበርና ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፋሲካ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ እንዲመጡ ፡ ከቤርሳቤህ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዳን ፡ ድረስ ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ አዋጅ ፡ እንዲነገር ፡ ወሰኑ ። ፮ እንደ ፡ ንጉሡም ፡ ትእዛዝ ፡ መልእክተኞቹ ፡ እንዲህ ፡ የሚለውን ፡ የንጉሡንና ፡ የአለቆቹን ፡ ደብዳቤ ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ እስራኤልና ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ ሄዱ ፡— የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔር ፡ ከአሦር ፡ ነገሥታት ፡ እጅ ፡ ወዳመለጠ ፡ ቅሬታችሁ ፡ እንዲመለስ ፡ ወደ ፡ አብርሃምና ፡ ወደ ፡ ይስሐቅ ፡ ወደ ፡ እስራኤልም ፡ አምላክ ፡ ተመለሱ ። ፯ እናንተም ፡ እንደምታዩ ፡ የተፈቱ ፡ እስኪያደርጋቸው ፡ ድረስ ፡ የአባቶቻቸውን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንደ ፡ በደሉ ፡ እንደ ፡ አባቶቻችሁና ፡ እንደ ፡ ወንድሞቻችሁ ፡ አትሁኑ ። ፰ አባቶቻችሁም ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ አንገተ ፡ ደንዳና ፡ አትሁኑ ፤ እጃችሁንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስጡ ፥ ለዘላለም ፡ ወደ ፡ ተቀደሰው ፡ ወደ ፡ መቅደሱም ፡ ግቡ ፥ ጽኑ ፡ ቍጣውም ፡ ከእናንተ ፡ እንዲመለስ ፡ አምላካችሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አምልኩ ። ፱ አምላካችሁም ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸርና ፡ መሐሪ ፡ ነውና ፥ ወደ ፡ እርሱም ፡ ብትመለሱ ፡ ፊቱን ፡ ከእናንተ ፡ አያዞርምና ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ብትመለሱ ፡ ወንድሞቻችሁና ፡ ልጆቻችሁ ፡ በማረኩአቸው ፡ ፊት ፡ ምሕረትን ፡ ያገኛሉ ፥ ደግሞም ፡ ወደዚህች ፡ ምድር ፡ ይመለሳሉ ።

፲ መልእክተኞቹም ፡ ከከተማ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ በኤፍሬምና ፡ በምናሴ ፡ አገር ፡ እስከ ፡ ዛብሎን ፡ ሄዱ ፤ እነዚያ ፡ ግን ፡ በንቀት ፡ ሳቁባቸው ፥ አፌዙባቸውም ። ፲፩ ነገር ፡ ግን ፡ ከአሴርና ፡ ከምናሴ ፡ ከዛብሎንም ፡ አያሌ ፡ ሰዎች ፡ ሰውነታቸውን ፡ አዋረዱ ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ መጡ ። ፲፪ ደግሞም ፡ አንድ ፡ ልብ ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ የሆነውን ፡ የንጉሡንና ፡ የአለቆቹን ፡ ትእዛዝ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ሆነ ።

፲፫ በሁለተኛውም ፡ ወር ፡ የቂጣውን ፡ በዓል ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ጉባኤ ፡ የሆነ ፡ ሕዝብ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተከማቸ ። ፲፬ ተነሥተውም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የነበሩትን ፡ መሠዊያዎችና ፡ ለጣዖታት ፡ የሚያጥኑበትን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ አስወገዱ ፥ በቄድሮንም ፡ ወንዝ ፡ ጣሉት ። ፲፭ በሁለተኛውም ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ ፋሲካውን ፡ አረዱ ፤ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑም ፡ አፈሩ ፥ ተቀደሱም ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ አመጡ ። ፲፮ እንደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሙሴ ፡ ሕግ ፡ በሥርዓታቸው ፡ ቆሙ ፤ ካህናቱም ፡ ከሌዋውያን ፡ እጅ ፡ የተቀበሉትን ፡ ደም ፡ ይረጩ ፡ ነበር ። ፲፯ በጉባኤውም ፡ ያልተቀደሱ ፡ እጅግ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ ስለዚህም ፡ ሌዋውያን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይቀድሱአቸው ፡ ዘንድ ፡ ንጹሐን ፡ ላልሆኑት ፡ ሁሉ ፡ ፋሲካውን ፡ ያርዱላቸው ፡ ነበር ። ፲፰ እንደ ፡ ትእዛዙም ፡ ሳይ

ሆን ፡ ከኤፍሬምና ፡ ከምናሴ ፡ ከይሳኮርና ፡ ከዛብሎንም ፡ ወገን ፡ እጅግ ፡ ሰዎች ፡ ሳይነጹ ፡ ፋሲካውን ፡ በሉ ። ፲፰ ሕዝቅያስም ፡— ምንም ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ማንጻት ፡ ባይነጻ ፡ የአባቶቹን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመፈለግ ፡ ልቡን ፡ የሚያቀናውን ፡ ሁሉ ፡ ቸሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቅር ፡ ይበለው ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ ጸለየ ። ፳ እግዚአብሔርም ፡ ሕዝቅያስን ፡ ሰማው ÷ ሕዝቡንም ፡ ፈወሰ ። ፳፩ በኢየሩሳሌምም ፡ ተገኝተው ፡ የነበሩ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የቂጣውን ፡ በዓል ፡ በታላቅ ፡ ደስታ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ አደረጉ ፤ ሌዋውያኑና ፡ ካህናቱም ፡ በዜማ ፡ ዕቃ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እየዘመሩ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግኑ ፡ ነበር ። ፳፪ ሕዝቅያስም ፡ በእግዚአብሔር ፡ አገልግሎት ፡ አስተዋዮች ፡ የነበሩትን ፡ ሌዋውያንን ፡ ሁሉ ፡ ያጽናና ፡ ነበር ። የደኅንነትንም ፡ መሥዋዕት ፡ እያቀረቡ ÷ የአባቶቻቸውንም ፡ አምላክ ፡ እያመሰገኑ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ አደረጉ ።

፳፫፡፳፬ የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ ሕዝቅያስ ፡ ስለ ፡ ቍርባን ፡ ሺህ ፡ ወይፈኖችና ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡ በጎች ፡ ለጉባኤው ፡ ሰጥቶ ፡ ነበርና ÷ አለቆቹም ፡ ሺህ ፡ ወይፈኖችና ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ በጎች ፡ ለጉባኤው ፡ ሰጥተው ፡ ነበርና ÷ ከካህናቱም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ተቀድሰው ፡ ነበርና ፡ ጉባኤው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ተማከሩ ፤ በደስታም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ አደረጉ ። ፳፭ የይሁዳም ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ÷ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑ ÷ ከእስራኤልም ፡ የመጡ ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ÷ ከእስራኤልም ፡ አገር ፡ የመጡትና ፡ በይሁዳ ፡ የኖሩት ፡ እንግዶች ፡ ደስ ፡ አላቸው ። ፳፮ በኢየሩሳሌምም ፡ ታላቅ ፡ ደስታ ፡ ሆነ ፤ ከእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ከዳዊት ፡ ልጅ ፡ ከሰሎሞን ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ በዓል ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አልተደረገም ፡ ነበር ። ፳፯ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑም ፡ ተነሥተው ፡ ሕዝቡን ፡ ባረኩ ፤ ድምፃቸውም ፡ ተሰማ ÷ ጸሎታቸውም ፡ ወደ ፡ ቅዱስ ፡ መኖሪያው ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ዐረገ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፩ ።

፩ ይህም ፡ ሁሉ ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ በዚያ ፡ የተገኙ ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ከተሞች ፡ ወጥተው ፡ ሁሉን ፡ ፈጽመው ፡ እስኪጠፉአቸው ፡ ድረስ ፤ ሐውልቶቹን ፡ሰባበሩ ÷ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶቹንም ፡ ቈረጡ ÷ በይሁዳና ፡ በብንያምም ፡ ሁሉ ፡ ደግሞም ፡ በኤፍሬምና ፡ በምናሴ ፡ የነበሩትን ፡ የኮረብታው ፡ መስገጃዎችና ፡ መሠዊያዎች ፡ አፈረሱ ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ርስታቸውና ፡ ወደ ፡ ከተሞቻቸው ፡ ተመለሱ ።

፪ ሕዝቅያስም ፡ የካህናትንና ፡ የሌዋውያንን ፡ ሰሞን ፡ በየክፍላቸውና ፡ በየአገልግሎታቸው ፡ አቆመ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አደባባይ ፡ በሮች ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የደኅንነቱን ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ÷ ያገለግሉም ፡ ዘንድ ÷ ያመሰግኑም ፡ ያከብሩም ፡ ዘንድ ፡ ካህናቱንና ፡ ሌዋውያኑን ፡ አቆመ ። ፫ በእግዚአብሔርም ፡ ሕግ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ በጥዋትና ፡ በማታ ÷ በሰንበታቱም ÷ በመባቻዎቹም ÷ በበዓላትም ፡ ለሚቀርበው ፡ ለሚቃጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ ንጉሡ ፡ ከገንዘቡ ፡ የሚከፍለውን ፡ ወሰነ ። ፬ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ለአገልግሎት ፡ እንዲጸኑ ፡ ለካህናቱና ፡ ለሌዋውያን ፡ ክፍላቸውን ፡ ይሰጡ ፡ ዘንድ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩትን ፡ ሕዝብ ፡ አዘዘ ። ፭ ይህንም ፡ ነገር ፡ እንዳዘዘ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የእህሉንና ፡ የወይኑን ፡ ጠጅ ፡ የዘይቱንና ፡ የማሩንም ÷ የእርሻውንም ፡ ፍሬ ፡ ሁሉ ፡ በኵራት ፡ ሰጡ ፤ የሁሉንም ፡ አሥራት ፡ አብዝተው ፡ አቀረቡ ። ፮ በይሁዳም ፡ ከተሞች ፡ የሚኖሩ ፡ የእስራኤልና ፡ የይሁዳ ፡ ልጆች ፡ የበሬውንና ፡ የበጉን ፡ አሥራት ÷ ለአምላካቸውም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰውን ፡ አሥራት ፡ አመጡ ÷ ክምረውም ፡ አኖሩት ። ፯ በሦስተኛው ፡ ወር ፡ መከመር ፡ ጀመሩ ፤ ፰ በሰባተኛውም ፡ ወር ፡ ጨረሱ ። ሕዝቅያስና ፡ አለቆቹም ፡ መጥተው ፡ ክምሩን ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርንና ፡ ሕዝቡን ፡ እስራኤልን ፡ ባረኩ ። ፱ ሕዝቅያስም ፡ ካህናቱንና ፡ ሌዋውያኑን ፡ ስለ ፡ ክምሩ ፡ ጠየቀ ። ፲ ከሳዶቅም ፡ ወገን ፡ የሆነ ፡ ዋነኛው ፡ ካህን ፡ ዓዛርያስ ፡— ሕዝቡ ፡ ቍርባኑን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ማቅረብ ፡ ከጀመረ ፡ ወዲህ ፡ በልተናል ÷ ጠግበናልም ÷ እግዚአብሔርም ፡ ሕዝቡን ፡ ባርኮአልና ፡ ብዙ ፡ ተርፎአል ፤ የተረፈውም ፡ ይህ ፡ ክምር ፡ ትልቅ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ።

፲፩ ሕዝቅያስም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ጐተራ ፡ ያዘጋጁ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ እነርሱም ፡ አዘጋጁ ። ፲፪ ቍርባኑንና ፡ አሥራቱን ፡ የተቀደሱትንም ፡ በእምነት ፡ ወደዚያ ፡ አገቡት ። ሌዋዊውም ፡ ኮናንያ ፡ ተሾመባቸው ÷ ወንድሙም ፡ ሰሜኢ ፡ በማዕርግ ፡ ሁለተኛ ፡ ነበረ ፤ ፲፫ በንጉሡም ፡ በሕዝቅያስና ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ በዓዛርያስ ፡ ትእዛዝ ፡ ይሒኤል ÷ ዓዛዝያ ÷ ናሐት ÷ አሣሄል ÷ ይሬሞት ÷ ዮዛባት ÷ ኤሊኤል ÷ ሰማኪያ ÷ መሐት ÷ በናያስ ÷ ከኮናንያና ፡ ከወንድሙ ፡ ከሰሜኢ ፡ እጅ ፡ በታች ፡ ተቈጣጣሪዎች ፡ ነበሩ ። ፲፬ የሌዋዊውም ፡ የይምና ፡ ልጅ ፡ የምሥራቁ ፡ ደጅ ፡ በረኛ ፡ ቆሬ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መባና ፡ የተቀደሱትን ፡ ነገሮች ፡ እንዲያከፍል ፡ ሕዝቡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በፈቃድ ፡ ባቀረቡት ፡ ላይ ፡ ተሾመ ። ፲፭ በካህናቱም ፡ ከተሞች ፡ ለታላላቆችና ፡ ለታናናሾች ፡ ወንድሞቻቸው ፡ በየሰሞናቸው ፡ ክፍላቸውን ፡ በእምነት ፡ ይሰጡ ፡ ዘንድ ፡ ዔድን ÷ ሚንያሚን ÷ ኢያሱ ÷ ሸማያ ÷ አማርያ ÷ ሴኬንያ ፡ ከእጁ ፡ በታች ፡ ነበሩ ። ፲፮ ከሦስትም ፡ ዓመት ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ላሉ ፡ በየሰሞናቸውም ፡ ለሥራቸውና ፡ ለአገልግሎታቸው ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ለሚ

፲፯ ገቡ ፡ ወንዶች ፡ ሁሉ ፤ በየአባቶቻቸውም ፡ ቤት ፡ ለተቈጠሩ ፡ ካህናት ÷ ከሀያ ፡ ዓመትም ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ላሉ ፡ በየሥርዓታቸውና ፡ በየሰሞ
፲፰ ናቸው ፡ ለተቈጠሩ ፡ ሌዋውያን ÷ በማኅበሩም ፡ ሁሉ ፡ በየትውልዳቸው ፡ ለተቈጠሩ ፡ ለሕፃና ቶቻቸውና ፡ ለሚስቶቻቸው ፡ ለወንዶችና ፡ ለሴ ቶች ፡ ልጆቻቸውም ፡ ይሰጡ ፡ ነበር ፤ በእም
፲፱ ነት ፡ ተቀድሰዋልና ። በየከተማይቱም ፡ ሁሉ ፡ በከተማቸው ፡ መሰምርያዎቹ ፡ ላሉ ፡ ለአሮን ፡ ልጆች ፡ ለካህናቱ ÷ ከካህናቱም ፡ ወገን ፡ ላሉ ፡ ወንዶች ፡ ሁሉ ÷ በትውልዳቸውም ፡ ለተቈ ጠሩ ፡ ሌዋውያን ፡ ሁሉ ፡ ክፍላቸውን ፡ ይሰጡ ፡ ዘንድ ፡ በስማቸው ፡ የተጻፉ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ።
፳ ሕዝቅያስም ፡ በይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ አደ ረገ ፤ በአምላኩም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ መልካምንና ፡ ቅንን ፡ ነገር ፡ እውነትንም ፡ አደ
፳፩ ረገ ። ስለ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ አገልግ ሎት ፡ በጀመረው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ÷ በሕጉና ፡ በት እዛዙም ÷ አምላኩን ፡ ለመፈለግ ፡ በፍጹም ፡ ልቡ ፡ አደረገው ÷ ተከናወነለትም ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

፩ ከዚህም ፡ ነገርና ፡ ከዚህ ፡ እምነት ፡ በኋላ ፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ሰናክሬም ፡ መጥቶ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ገባ ÷ በተመሸጉትም ፡ ከተሞች ፡ ፊት ፡
፪ ሰፈረ ÷ ሊወስዳቸውም ፡ አሰበ ። ሕዝቅያስም ፡ ሰናክሬም ፡ እንደ ፡ መጣ ÷ ኢየሩሳሌምንም ፡
፫ ሊወጋ ፡ ፊቱን ፡ እንዳቀና ፡ በየ ፡ ጊዜ ÷ ከከተ ማይቱ ፡ በስተ ፡ ውጭ ፡ ያለውን ፡ የውኃውን ፡ ምንጭ ፡ ይደፍኑ ፡ ዘንድ ፡ ከአለቆቹና ፡ ከኃያ
፬ ላኑ ፡ ጋር ፡ ተማከረ ፤ እነርሱም ፡ ረዱት ። እጅ ግም ፡ ሰዎች ፡ ተሰብስበው ፦ የአሦር ፡ ነገሥ ታት ፡ መጥተው ፡ ብዙ ፡ ውኃ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ያገ ኛሉ ? ብለው ፡ ምንጮችን ፡ ሁሉ ÷ በምድርም ፡ መካከል ፡ ይጐርፍ ፡ የነበረውን ፡ ወንዝ ፡
፭ ደፈኑ ። ሰውነቱንም ፡ አጸናና ÷ የፈረሰውንም ፡ ቅጥር ፡ ሁሉ ፡ ጠገነ ÷ በላዩም ፡ ግንብ ፡ ሠራ በት ÷ ከእርሱም ፡ በስተ ፡ ውጭ ፡ ሌላ ፡ ቅጥር ፡ ሠራ ፤ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ያለችውን ፡ ሚሎን ፡ አጠነከረ ፤ ብዙም ፡ መሣሪያና ፡ ጋሻ ፡ ሠራ ።
፮ የጦር ፡ አለቆቹንም ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ሾሞ ÷ ሁሉንም ፡ በከተማይቱ ፡ በር ፡ ወዳለው ፡ አደባ
፯ በይ ፡ ሰብስቦ ፦ ጽኑ ÷ አይዞአችሁ ፤ ከእኛም ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ካለው ፡ ይበልጣ ልና ፡ ከአሦር ፡ ንጉሥና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ካለው ፡ ጭፍራ ፡ ሁሉ ፡ አትፍሩ ÷ አትደንግጡም ።
፰ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የሥጋ ፡ ክንድ ፡ ነው ፤ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ ግን ፡ የሚረዳንና ፡ የሚዋጋልን ፡ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ አጸ ናናቸው ። ሕዝቡም ፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በሕ ዝቅያስ ፡ ቃል ፡ ተጽናና ።
፱ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ሰናክሬም ፡ ከሠራዊቱ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ በለኪሶ ፡ ፊት ፡ ሳለ ፡ ባሪያዎቹን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ሕዝቅያስና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ነበሩ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ላከ ፦ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ሰናክሬም ፡
፲ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እናንተ ፡ በማን ፡ ተማምና ችሁ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ምሽግ ፡ ትቀመጣላችሁ ?
፲፩ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአሦር ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ ያድነናል ፡ እያለ ፡ በራብና ፡ በጥም ፡ እን ድትሞቱ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣችሁ ፡ ዘንድ ፡ የሚ ያባብላችሁ ፡ ሕዝቅያስ ፡ አይደለምን ? በአንድ ፡
፲፪ መሠዊያ ፡ ፊት ፡ ስገዱ ÷ በእርሱም ፡ ላይ ፡ ዕጠኑ ፡ እያለ ፡ ይሁዳንና ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ አዝዞ ÷ የኮ ረብታው ፡ መስገጃዎቹና ፡ መሠዊያዎቹን ፡ ያፈ ረሰ ፡ ይህ ፡ ሕዝቅያስ ፡ አይደለምን ? እኔና ፡
፲፫ አባቶቼ ፡ በምድር ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ያደረግነ ውን ፡ አላወቃችሁምን ? የምድርስ ፡ ሁሉ ፡ አሕ ዛብ ፡ አማልክት ፡ አገራቸውን ፡ ከእጄ ፡ ያድኑ ፡ ዘንድ ፡ በውኑ ፡ ተቻላቸውን ? አምላካችሁስ ፡
፲፬ ከእጄ ፡ እናንተን ፡ ለማዳን ፡ ይችል ፡ ዘንድ ፡ አባ ቶቼ ፡ ካጠፉአቸው ፡ ከአሕዛብ ፡ አማልክት ፡ ሁሉ ፡ ሕዝቡን ፡ ከእጄ ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ የቻለ ፡ ማን ፡ ነው ? አሁንም ፡ ሕዝቅያስ ፡ አያስታችሁ ÷
፲፭ እንዲህም ፡ አያባብላችሁ ÷ አትመኑትም ፤ ከአ ሕዛብና ፡ ከመንግሥታት ፡ አማልክት ፡ ሁሉ ፡ ሕዝቡን ፡ ከእጄና ፡ ከአባቶቼ ፡ እጅ ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ ማንም ፡ አልቻለም ፤ ይልቁንስ ፡ አምላ ካችሁ ፡ ከእጄ ፡ ያድናችሁ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ይችላል ?
፲፮ ባሪያዎቹም ፡ ደግሞ ፡ በአምላክ ፡ በእግዚአ ብሔርና ፡ በባሪያው ፡ በሕዝቅያስ ፡ ላይ ፡ ሌላ ፡
፲፯ ብዙ ፡ ነገር ፡ ተናገሩ ። ደግሞም ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመሰደብ ÷ በእር ሱም ፡ ላይ ፡ ለመናገር ፦ የምድር ፡ አሕዛብ ፡ አማልክት ፡ ሕዝባቸውን ፡ ከእጄ ፡ ያድኑ ፡ ዘንድ ፡ እንዳልቻሉ ÷ እንዲሁ ፡ የሕዝቅያስ ፡ አምላክ ፡ ሕዝቡን ፡ ከእጄ ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ አይችልም ፡ የሚል ፡ ደብዳቤ ፡ ጻፈ ። ከተማይቱንም ፡ እን
፲፰ ዲወስዱ ÷ በቅጥር ፡ ላይ ፡ የተቀመጡትን ፡ የኢ የሩሳሌም ፡ ሕዝብ ፡ ያስፈሩና ፡ ያስደነግጡ ፡ ዘንድ ÷ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ በዕብራይስጥ ፡ ቋንቋ ፡ ይጮኹባቸው ፡ ነበር ። በሰውም ፡ እጅ ፡ በተ
፲፱ ሠሩ ፡ በምድር ፡ አሕዛብ ፡ አማልክት ፡ ላይ ፡ እን ደሚናገሩ ፡ መጠን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አምላክ ፡ ላይ ፡ ተናገሩ ።
፳ ንጉሡም ፡ ሕዝቅያስና ፡ የአሞጽ ፡ ልጅ ፡ ነቢዩ ፡ ኢሳይያስ ፡ ስለዚህ ፡ ጸለዩ ÷ ወደ ፡ ሰማ
፳፩ ይም ፡ ጮኹ ። እግዚአብሔርም ፡ ጽኑዓን ፡ ኃያላኑንና ፡ መሳፍንቱን ፡ አለቆቹንም ፡ ከአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ሰፈር ፡ እንዲያጠፉ ፡ መልአኩን ፡ ሰደደ ። የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ አፍሮ ፡ ወደ ፡ አገሩ ፡ ተመለሰ ። ወደ ፡ አምላኩም ፡ ቤት ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ከወገቡ ፡ የወጡት ፡ ልጆቹ ፡ በዚያ ፡
፳፪ በሰይፍ ፡ ገደሉት ። እንዲሁም ፡ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቅያስንና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩትን ፡ ከአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ከሰናክሬም ፡ እጅ ፡ ከሁሉም ፡

እጅ ፡ አዳናቸው ፤ በዙሪያቸውም ፡ ካለው ፡
፳፫፤ ሁሉ ፡ አሳረፋቸው ። ብዙዎቹም ፡ ለእግዚአ
ብሔር ፡ መባ ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
ይመጡ ፡ ነበር ፥ ለይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ ለሕዝቅ
ያስ ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ይሰጡ ፡ ነበር ፤ እርሱም ፡
ከዚህ ፡ ነገር ፡ በኋላ ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡
ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ።

፳፬፤ በዚያም ፡ ወራት ፡ ሕዝቅያስ ፡ እስኪሞት ፡
ድረስ ፡ ታመመ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡
ጸለየ ፤ እርሱም ፡ ተናገረው ፥ ምልክትም ፡
፳፭፤ ሰጠው ። ሕዝቅያስ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ተቀበለው ፡
ቸርነት ፡ መጠን ፡ አላደረገም ፥ ልቡም ፡ ኰራ ፤
ስለዚህም ፡ በእርሱና ፡ በይሁዳ ፡ በኢየሩሳሌ
፳፮፤ ምም ፡ ላይ ፡ ቍጣ ፡ ሆነ ። ሕዝቅያስም ፡ ከኢየ
ሩሳሌም ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ስለ ፡ ልቡ ፡ ኵራት ፡
ሰውነቱን ፡ አዋረደ ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡
በሕዝቅያስ ፡ ዘመን ፡ አልመጣባቸውም ።

፳፯፤ ለሕዝቅያስም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ሀብትና ፡
ክብር ፡ ነበረው ፤ ለብርና ፡ ለወርቅም ፥ ለከበ
ረው ፡ ዕንቍና ፡ ለሽቱው ፥ ለጋሻውና ፡ ለከበ
ረው ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ግምጃ ፡ ቤቶች ፡ ሠራ ።
፳፰፤ ለእህልና ፡ ለወይን ፡ ጠጅም ፡ ለዘይትም ፡ ዕቃ ፡
ቤቶች ፥ ለልዩ ፡ ልዩም ፡ እንስሳ ፡ ጋጥ ፥ ለመ
፳፱፤ ንጎችም ፡ በረት ፡ ሠራ ። እግዚአብሔርም ፡
እጅግ ፡ ብዙ ፡ ጥሪት ፡ ሰጥቶት ፡ ነበርና ፡ ከተ
ሞችን ፡ ሠራ ፥ ብዙም ፡ የበግና ፡ የላም ፡ መንጋ ፡
፴፤ ሰበሰበ ። ይህም ፡ ሕዝቅያስ ፡ የላይኛውን ፡ የግ
ዮንን ፡ ውኃ ፡ ምንጭ ፡ ደፈነ ፥ በዳዊትም ፡
ከተማ ፡ በምዕራብ ፡ በኩል ፡ አቅንቶ ፡ አወረ
ደው ። የሕዝቅያስም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ተከናወነ ።
፴፩፤ ነገር ፡ ግን ፡ የባቢሎን ፡ መሳፍንት ፡ መልእክተ
ኞች ፡ በአገሩ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ተደረገው ፡ ተአም
ራት ፡ ይጠይቁት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ በተ
ላኩ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይፈትነውና ፡ በልቡ ፡
ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፡ ተወው ።

፴፪፤ የሕዝቅያስም ፡ የቀረው ፡ ነገር ፥ ቸርነቱም ፥
እነሆ ፥ በአሞጽ ፡ ልጅ ፡ በነቢዩ ፡ በኢሳይያስ ፡
ራእይ ፡ በይሁዳና ፡ በእስራኤልም ፡ ነገሥታት ፡
፴፫፤ መጽሐፍ ፡ ተጽፎአል ። ሕዝቅያስም ፡ ከአበ
ቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በዳዊትም ፡ ልጆች ፡
መቃብር ፡ በላይኛው ፡ ክፍል ፡ ቀበሩት ፤ በይ
ሁዳና ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡
በሞቱ ፡ አከበሩት ። ልጁም ፡ ምናሴ ፡ በእርሱ ፡
ፋንታ ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፫ ።

፩፤ ምናሴም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የአ
ሥራ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩ
ሳሌምም ፡ አምሳ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ።
፪፤ እግዚአብሔርም ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡
እንዳወጣቸው ፡ እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ያለ ፡ ርኵ
ሰት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡
፫፤ አደረገ ። አባቱም ፡ ሕዝቅያስ ፡ ያፈረሳቸውን ፡
የኮረብታውን ፡ መስገጃዎች ፡ መልሶ ፡ ሠራ ፤
ለበአሊምም ፡ መሠዊያ ፡ ሠራ ፥ የማምለኪያ ፡
ዐፀዶችንም ፡ ተከለ ፥ ለሰማይም ፡ ሠራዊት ፡
፬፤ ሁሉ ፡ ሰገደ ፥ አመለካቸውም ። እግዚአብሔ
ርም ፡ — ስሜ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለዘላለም ፡ ይኖ
ራል ፡ ባለው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ መሠዊ
፭፤ ያዎችን ፡ ሠራ ። በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡
በሁለቱ ፡ አደባባዮች ፡ ላይ ፡ ለሰማይ ፡ ሠራዊት ፡
፮፤ ሁሉ ፡ መሠዊያዎችን ፡ ሠራ ። በሄኖምም ፡
ልጅ ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ ልጆቹን ፡ በእሳት ፡ አሳ
ለፈ ፤ ሞራ ፡ ገላጭም ፡ ሆነ ፥ አስማትም ፡ አደ
ረገ ፥ መተተኛም ፡ ነበረ ፥ መናፍስት ፡ ጠሪዎ
ችንና ፡ ጠንቋዮችንም ፡ ሰበሰበ ፤ ያስቈጣውም ፡
ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እጅግ ፡ ክፉ ፡
፯፡፰፤ ነገር ፡ አደረገ ። እግዚአብሔርም ፡ ለዳዊትና ፡
ለልጁ ፡ ለሰሎሞን ፡ — በዚህ ፡ ቤት ፡ ከእስራኤ
ልም ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ በመረጥኋት ፡ በኢየሩሳሌም ፡
ስሜን ፡ ለዘላለም ፡ አኖራለሁ ፤ ያዘዝኋቸው
ንም ፡ ሁሉ ፥ በሙሴ ፡ የተሰጠውን ፡ ሕግና ፡
ሥርዓት ፡ ፍርድንም ፡ ሁሉ ፡ ቢያደርጉ ፡ ቢጠ
ብቁም ፥ ለአባቶቻችሁ ፡ ከሰጠኋት ፡ ምድር ፡
የእስራኤልን ፡ እግር ፡ እንደ ፡ ገና ፡ አላርቅም ፡
ባለበት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ የሠራ
ውን ፡ የጣዖት ፡ የተቀረጸውን ፡ ምስል ፡ አቆመ ።
፱፤ ምናሴም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ፊት ፡ ካጠፋቸው ፡ ከአሕዛብ ፡ ይልቅ ፡ ክፉ ፡
ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሚ
ኖሩትን ፡ አሳተ ።

፲፤ እግዚአብሔርም ፡ ምናሴንና ፡ ሕዝቡን ፡ ተና
፲፩፤ ገራቸው ፤ ግን ፡ አልሰሙትም ። ስለዚህም ፡
እግዚአብሔር ፡ የአሦርን ፡ ንጉሥ ፡ ሠራዊት ፡
አለቆች ፡ አመጣባቸው ፤ ምናሴንም ፡ በዛንጅር ፡
ያዙት ፥ በሰንሰለትም ፡ አስረው ፡ ወደ ፡ ባቢ
፲፪፤ ሎን ፡ ወሰዱት ። በተጨነቀም ፡ ጊዜ ፡ አምላ
ኩን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈለገ ፥ በአባቶቹም ፡
አምላክ ፡ ፊት ፡ ሰውነቱን ፡ እጅግ ፡ አዋረደ ።
፲፫፤ ወደ ፡ እርሱም ፡ ጸለየ ፤ እርሱም ፡ ተለመነው ፥
ጸሎቱንም ፡ ሰማው ፥ ወደ ፡ መንግሥቱም ፡
ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መለሰው ፤ ምናሴም ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እርሱ ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
አወቀ ።

፲፬፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በዳዊት ፡ ከተማ ፡ በስተ ፡
ውጭው ፡ ከግዮን ፡ ምዕራብ ፡ በሸለቆው ፡
ውስጥ ፡ እስከ ፡ ዓሣ ፡ በር ፡ መግቢያ ፡ ድረስ ፡
ቅጥር ፡ ሠራ ። በዖፌልም ፡ አዞረበት ፥ እጅግም ፡
ከፍ ፡ አደረገው ፤ በተመሸጉትም ፡ በይሁዳ ፡
ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ የጭፍራ ፡ አለቆችን ፡ አኖረ ።
፲፭፤ እንግዶችንም ፡ አማልክትና ፡ ጣዖቱንም ፡ ከእ
ግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አራቀ ፥ የእግዚአብሔርም ፡
ቤት ፡ ባለበት ፡ ተራራ ፡ ላይና ፡ በኢየሩሳሌም ፡
የሠራቸውን ፡ መሠዊያዎች ፡ ሁሉ ፡ ወስዶ ፡
፲፮፤ ከከተማይቱ ፡ በስተ ፡ ውጭ ፡ ጣላቸው ። የእግዚ
አብሔርንም ፡ መሠዊያ ፡ ደግሞ ፡ አደሰ ፥ የደ
ኅንነትንና ፡ የምስጋናንም ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዋ
በት ፤ ይሁዳም ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ እግ

፲፯ ዚአብሔርን ፡ እንዲያመልኩ ፡ አዘዘ ። ሕዝቡ ፡ ግን ፡ ገና ፡ በከረብታው ፡ መስገጃዎች ፡ ይሠዋ ፡ ነበር ፤ ቢሆንም ፡ ለአምላኩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ብቻ ፡ ነበረ ።

፲፰ የምናሴም ፡ የቀረው ፡ ነገር ፥ ወደ ፡ አምላኩም ፡ የጸለየው ፡ ጸሎት ፥ በእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የነገሩት ፡ የነቢያት ፡ ቃል ፥ እነሆ ፥ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፎአል ። ፲፱ ደግሞም ፡ ጸሎቱ ፥ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተለመነው ፥ ኃጢአቱና ፡ መተላለፉ ፡ ሁሉ ፥ ራሱንም ፡ ሳያዋርድ ፡ የከረብታው ፡ መስገጃዎችን ፡ የሠራበት ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀዱንና ፡ የተቀረጹትንም ፡ ምስሎች ፡ የተከለበት ፡ ስፍራ ፥ እነሆ ፥ በባለ ፡ ራእዩ ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፎአል ። ፳ ምናሴም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋር ፡ አንቀላፋ ፥ በቤቱም ፡ ቀበሩት ፤ ልጁም ፡ አሞጽ ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

፳፩ አሞጽ ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። ፳፪ አባቱም ፡ ምናሴ ፡ እንዳደረገ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ፤ አሞጽም ፡ አባቱ ፡ ምናሴ ፡ ለሠራቸው ፡ ለተቀረጹት ፡ ምስሎች ፡ ሁሉ ፡ ሠዋ ፥ አመለካቸውም ። ፳፫ አባቱም ፡ ምናሴ ፡ ሰውነቱን ፡ እንዳዋረደ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሰውነቱን ፡ አላዋረደም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አሞጽ ፡ መተላለፉን ፡ አጅግ ፡ አበዛ ። ፳፬ ባሪያዎቹም ፡ ተማምለው ፡ በቤቱ ፡ ገደሉት ። ፳፭ የአገሩ ፡ ሕዝብ ፡ ግን ፡ በንጉሡ ፡ በአሞጽ ፡ ላይ ፡ የተማማሉትን ፡ ሁሉ ፡ ገደሉ ፤ የአገሩም ፡ ሕዝብ ፡ ልጁን ፡ ኢዮስያስን ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ አነገሡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፬ ።

፩ ኢዮስያስም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የስምንት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ሠላሳ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። ፪ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አደረገ ፥ በአባቱም ፡ በዳዊት ፡ መንገድ ፡ ሄደ ፤ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ አላለም ። ፫ በነገሠም ፡ በስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ ገና ፡ ብላቴና ፡ ሳለ ፡ የአባቱን ፡ የዳዊትን ፡ አምላክ ፡ ይፈልግ ፡ ጀመር ፤ በአሥራ ፡ ሁለተኛውም ፡ ዓመት ፡ ይሁዳንና ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ከከረብታው ፡ መስገጃዎችና ፡ ከማምለኪያ ፡ ዐፀዶቹ ፥ ከተቀረጹትና ፡ ቀልጠው ፡ ከተሠሩት ፡ ምስሎች ፡ ያነጻ ፡ ጀመር ። ፬ የበአሊምንም ፡ መሠዊያዎች ፡ በፊቱ ፡ አፈረሱ ፤ በላዩም ፡ የነበሩትን ፡ የፀሐዩን ፡ ምስሎች ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶቹንም ፡ ቈረጠ ፤ የተቀረጹትንና ፡ ቀልጠው ፡ የተሠሩትን ፡ ምስሎች ፡ ሰባበረ ፥ አደቀቀቸውም ፥ ይሠዉላቸው ፡ በነበሩት ፡ ሰዎች ፡ መቃብርም ፡ ላይ ፡ በተናቸው ። ፭ የካህናቶቻቸውንም ፡ አጥንት ፡ በመሠዊያቸው ፡ ላይ ፡ አቃጠለ ፤ ይሁዳንና ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ አነጻ ። ፮ የምናሴንና ፡ የኤፍሬምንም ፡ የስምዖንና ፡ የንፍታሌምንም ፡ ከተሞች ፥ በዙሪያቸውም ፡ ያለውን ፡ በታ ፡ እንዲሁ ፡ አነጻ ። ፯ መሠዊያዎቹንም ፡ አፈረሰ ፥ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶቹንና ፡ የተቀረጹትን ፡ ምስሎች ፡ አደቀቀ ፥ በእስራኤልም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ የፀሐዩን ፡ ምስሎች ፡ ሁሉ ፡ ቈራረጠ ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ተመለሰ ።

፰ በነገሠም ፡ በአሥራ ፡ ስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ ምድሪቱንና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ካነጻ ፡ በኋላ ፥ የኤዜልያስ ፡ ልጅ ፡ ሳፋን ፥ የከተማይቱም ፡ አለቃ ፡ መዕሤያ ፥ ታሪክ ፡ ጸሐፊም ፡ የኢዮአካዝ ፡ ልጅ ፡ ኢዮአክ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የአምላኩን ፡ ቤት ፡ ይጠግኑ ፡ ዘንድ ፡ ሰደዳቸው ። ፱ ወደ ፡ ታላቁም ፡ ካህን ፡ ወደ ፡ ኬልቅያስ ፡ መጡ ፤ ሌዋውያኑም ፡ በረኞች ፡ ከምናሴና ፡ ከኤፍሬም ፡ ከቀረውም ፡ ከእስራኤል ፡ ሁሉ ፥ ከይሁዳና ፡ ከብንያም ፡ ሁሉ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ ከሚኖሩት ፡ የሰበሰቡትን ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የቀረበውን ፡ ገንዘብ ፡ ሰጡት ። ፲ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ በሚሠሩት ፡ ላይ ፡ ለተሾሙት ፡ ሰጡ ፤ እነርሱም ፡ ይጠግኑና ፡ ያድሱ ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ለሚሠሩ ፡ ሠራተኞች ፡ ሰጡ ። ፲፩ የይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ላፈረሱት ፡ ቤት ፡ ሰረገሎች ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፥ ለማጋጠሚያም ፡ እንጨት ፡ የተጠረበውንም ፡ ድንጋይ ፡ ይገዙ ፡ ዘንድ ፡ ለአናጢዎችና ፡ ለጠራቢዎች ፡ ሰጡ ።

፲፪ ሰዎቹም ፡ ሥራውን ፡ በመታመን ፡ አደረጉ ፤ በእነርሱም ፡ ላይ ፡ የተሾሙት ፥ ሥራውንም ፡ የሚያሠሩት ፡ ሌዋውያን ፡ ከሜራሪ ፡ ልጆች ፡ ኢኤትና ፡ አብድዩ ፥ ከቀዓትም ፡ ልጆች ፡ ዘካርያስና ፡ ሚሱላም ፡ ነበሩ ። ከሌዋውያንም ፡ ወገን ፡ በዜማ ፡ ዕቃ ፡ አዋቂዎች ፡ የነበሩ ፡ ሁሉ ፡ ፲፫ በተሸካሚዎችና ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ሥራ ፡ በሚሠሩ ፡ ላይ ፡ ተሾመው ፡ ነበር ፤ ጸሐፊዎቹና ፡ አለቆቹም ፡ በረኞቹም ፡ ከሌዋውያን ፡ ወገን ፡ ነበሩ ።

፲፬ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ የቀረበውን ፡ ገንዘብ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ካህኑ ፡ ኬልቅያስ ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ የተሰጠውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ አገኘ ። ፲፭ ኬልቅያስም ፡ ጸሐፊውን ፡ ሳፋንን ፦ የሕጉን ፡ መጽሐፍ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አግኝቼአለሁ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ። ኬልቅያስም ፡ መጽሐፉን ፡ ለሳፋን ፡ ሰጠው ። ፲፮ ሳፋንም ፡ መጽሐፉን ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ አመጣ ፤ ለንጉሡም ፦ ባሪያዎችህ ፡ የተሰጣቸውን ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ያደርጋሉ ፤ ፲፯ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ የተገኘውን ፡ ገንዘብ ፡ አፈሰሱ ፥ በሥራውም ፡ ላይ ፡ ለተሾሙትና ፡ ለሠራተኞቹ ፡ ሰጡ ፡ ብሎ ፡ አወራለት ። ፲፰ ጸሐፊውም ፡ ሳፋን ፡ ለንጉሡ ፦ ካህኑ ፡ ኬልቅያስ ፡ መጽሐፍ ፡ ሰጠኝ ፡ ብሎ ፡ ነገረው ። ሳፋንም ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ አነበበው ። ፲፱ ንጉሡም ፡ የሕጉን ፡ ቃል ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ልብሱን ፡ ቀደደ ። ፳ ንጉሡም ፡ ኬልቅያስን ፥ የሳፋንንም ፡ ልጅ ፡ አኪቃምን ፥ የሚክያስንም ፡ ልጅ ፡ ዓብዶንን ፥

ጽሐፈውንም ፡ ሳፋንን ÷ የንጉሡንም ፡ ብላቴና ፡ ፳፩ ዓሳያን ፡— በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈውን ፡ ሁሉ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አባቶቻችን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስላልጠበቁ ÷ በላያችን ፡ የነደደ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ እጅግ ፡ ነውና ፡ ሄዳችሁ ፡ ስለ ፡ ተገኘው ፡ የመጽሐፍ ፡ ቃል ፡ ለእኔ ፡ በእስራኤልና ፡ በይሁዳም ፡ ለቀሩት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠይቁ ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ።

፳፪ ኬልቅያስና ፡ እነዚያ ፡ ንጉሡ ፡ ያዘዛቸው ፡ ወደ ፡ ልብስ ፡ ጠባቂው ፡ ወደ ፡ ሐስራ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ቲቁዋ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ሴሌም ፡ ሚስት ፡ ወደ ፡ ነቢይቱ ፡ ወደ ፡ ሕልዳና ፡ ሄዱ ፤ እርስዋም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በከተማይቱ ፡ በሁለተኛው ፡ ክፍል ፡ ተቀምጣ ፡ ነበር ፤ ይህንም ፡ ነገር ፡ ፳፫ ነገሩአት ። እርስዋም ፡ አለቻቸው ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ወደ ፡ እኔ ፡ ለላካችሁ ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ፳፬ ብላችሁ ፡ ንገሩት ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ፊት ፡ በተነበበው ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፉትን ፡ ቃላት ፡ ሁሉ ÷ ማለት ፡ ክፉ ፡ ነገርን ÷ በዚህ ፡ ስፍራና ፡ በሚኖ ፳፭ ሩበት ፡ ላይ ፡ አመጣለሁ ። በእጃቸው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ሊያስቈጡኝ ፡ ትተውኛልና ÷ ለሌሎችም ፡ አማልክት ፡ ዐጥነዋልና ፡ ቍጣዬ ፡ በዚህ ፡ ፳፮ ስፍራ ፡ ላይ ፡ ይነድዳል ÷ አይጠፋምም ። እግዚአብሔርን ፡ ለመጠየቅ ፡ ለላካችሁ ፡ ለይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ እንዲህ ፡ በሉት ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ስለ ፡ ፳፯ ሰማኸው ፡ ቃል ÷ ልብህ ፡ ገር ፡ ሆኖአልና ÷ በፊቴም ፡ ራስህን ፡ አዋርደሃልና ÷ በዚህም ፡ ስፍራና ፡ በሚኖሩበት ፡ ላይ ፡ ቃሌን ፡ በሰማህ ፡ ጊዜ ፡ ራስህን ፡ አዋርደሃልና ÷ ልብስህንም ፡ ቀድደህ ፡ በፊቴ ፡ አልቅሰሃልና ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ ፳፰ ሰምቼሃለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። እነሆ ÷ ወደ ፡ አባቶችህ ፡ እሰበስብሃለሁ ÷ በሰላምም ፡ ወደ ፡ መቃብርህ ፡ ትሰበሰባለህ ፤ በዚህም ፡ ስፍራና ፡ በሚኖሩበት ፡ ላይ ፡ የማመጣውን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ዓይኖችህ ፡ አያዩም ። ይህንም ፡ ለንጉሡ ፡ አወሩለት ።

፳፱ ንጉሡም ፡ ላከ ÷ የይሁዳንና ፡ የኢየሩሳሌም ፴ ንም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰበ ። ንጉሡም ÷ የይሁዳም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ÷ በኢየሩሳሌምም ፡ የሚኖሩና ፡ ካህናቱ ÷ ሌዋውያኑም ÷ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ከታናሹ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ወጡ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ የተገኘውን ፡ የቃል ፡ ኪዳኑን ፡ መጽሐፍ ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ በጆሮአቸው ፡ አነበበ ። ፴፩ ንጉሡም ፡ በስፍራው ፡ ቆሞ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተከትሎ ፡ እንዲሄድ ÷ ትእዛዙንና ፡ ምስክሩን ፡ ሥርዓቱንም ፡ በፍጹም ፡ ልቡና ፡ በፍጹም ፡ ነፍሱ ፡ እንዲጠብቅ ÷ በዚህም ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈውን ፡ የቃል ፡ ኪዳን ፡ ቃል ፡ እንዲያደርግ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረገ ። ፴፪ በኢየሩሳሌምና ፡ በብንያምም ፡ የተገኙትን ፡ ሁሉ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ አማለ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ የሚኖሩት ፡ የአባቶቻቸው ፡ አምላክ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ እንዳዘዘ ፡ አደረጉ ። ፴፫ ኢዮስያስም ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ርኩሱን ፡ ሁሉ ፡ አስወገደ ÷ በእስራኤልም ፡ የተገኙትን ፡ ሁሉ ፡ አምላካቸውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዲያመልኩ ፡ አደረገ ። በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ የአባቶቻቸውን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከመከተል ፡ አልራቁም ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፭ ።

፩ ኢዮስያስም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ፋሲካ ፡ አደረገ ፤ በመጀመሪያውም ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ ፋሲካውን ፡ አረዱ ። ፪ ካህናቱንም ፡ በየሥርዓታቸው ፡ አቆመ ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡ አጸናናቸው ። ፫ እስራኤልንም ፡ ሁሉ ፡ ያስተምሩ ፡ ለነበሩት ÷ ለእግዚአብሔርም ፡ ለተቀደሱት ፡ ሌዋውያን ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ቅዱሱን ፡ ታቦት ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ ሰሎሞን ፡ በሠራው ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ አኑሩት ፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በትከሻችሁ ፡ ላይ ፡ ሸክም ፡ አይሆንባችሁም ፤ አሁንም ፡ አምላካችሁን ፡ እግዚአብሔርንና ፡ ሕዝቡን ፡ እስራኤልን ፡ አገልግሉ ፤ ፬ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ እንደ ፡ ጻፈው ፡ ልጁም ፡ ሰሎሞን ፡ እንደ ፡ ጻፈው ፡ በየሰሞናችሁና ፡ በየአባቶቻችሁ ፡ ቤቶች ፡ ተዘጋጁ ፤ ፭ እንደ ፡ ሕዝቡም ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ወንድሞቻችሁ ፡ በየአባቶች ፡ ቤቶች ፡ ሆናችሁ ፡ በመቅደሱ ፡ ቁሙ ፤ የሌዋውያንም ፡ ነገድ ፡ በየወገናቸው ፡ እንደ ፡ ተከፈሉ ፡ እናንተ ፡ ተከፈሉ ፤ ፮ ፋሲካውንም ፡ እረዱ ÷ እናንተም ፡ ተቀደሱ ÷ እግዚአብሔርም ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ለወንድሞቻችሁ ፡ አዘጋጁ ።

፯ ኢዮስያስም ፡ ለፋሲካው ፡ መሥዋዕት ፡ እንዲሆን ፡ በዚያ ፡ ለነበሩት ፡ ለሕዝቡ ፡ ልጆች ፡ ከመንጋው ፡ ሠላሳ ፡ ሺህ ፡ የበግና ፡ የፍየል ፡ ጠቦቶች ÷ ሦስት ፡ ሺህም ፡ ወይፈኖች ፡ ሰጣቸው ፤ እነዚህም ፡ ከንጉሡ ፡ ሀብት ፡ ነበሩ ። ፰ መሳፍንቱም ፡ ለሕዝቡና ፡ ለካህናቱ ፡ ለሌዋውያኑም ፡ በፈቃዳቸው ፡ ሰጡ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ አለቆች ÷ ኬልቂያስ ÷ ዘካርያስ ÷ ይሒኤል ÷ ለፋሲካው ፡ መሥዋዕት ፡ እንዲሆን ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ በጎችና ፡ ፍየሎች ÷ ሦስት ፡ መቶም ፡ በሬዎች ፡ ለካህናቱ ፡ ሰጡ ። ፱ የሌዋውያኑም ፡ አለቆች ፡ ኮናንያ ÷ ወንድሞቹም ፡ ሸማያና ፡ ናትናኤል ÷ ሐሸቢያ ÷ ይዒኤል ÷ ዮዛባት ፡ ለፋሲካው ፡ መሥዋዕት ፡ እንዲሆን ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ በጎችና ፡ ፍየሎች ÷ አምስት ፡ መቶም ፡ በሬዎች ፡ ለሌዋውያን ፡ ሰጡ ።

፲ አገልግሎቱም ፡ ተዘጋጀ ÷ ካህናቱም ፡ በስፍራቸው ÷ ሌዋውያኑም ፡ በየክፍላቸው ፡ እንደ ፡ ንጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ ቆሙ ። ፲፩ ፋሲካውንም ፡ አረዱ ÷

ሌዋውያኑም ፡ ቁርበቱን ፡ ገፈፉ ፥ ካህናቱም ፡
፲፪ ከእጃቸው ፡ የተቀበሉትን ፡ ደም ፡ ረጩ ። በሙ
ሴም ፡ መጽሐፍ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡
ለሕዝቡ ፡ ልጆች ፡ እንዲሰጡ ፡ የሚቃጠለውን ፡
መሥዋዕት ፡ ለዩ ። እንዲሁም ፡ በበሬዎቹ ፡ አደ
፲፫ ረጉ ። ፋሲካውንም ፡ እንደ ፡ ሥርዓቱ ፡ በእ
ሳት ፡ ጠበሱ ፤ የተቀደሰውንም ፡ ቍርባን ፡ በም
ንቸትና ፡ በሰታቴ ፡ በድስትም ፡ ቀቀሉ ፥ ለሕ
ዝቡም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ በፍጥነት ፡ አደረሱ ።
፲፬ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ለራሳቸውና ፡ ለካህናቱ ፡ አዘ
ጋጁ ፤ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ካህናቱ ፡ የሚቃ
ጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ ስቡን ፡ ለማቅረብ ፡
እስከ ፡ ሌሊት ፡ ድረስ ፡ ይሠሩ ፡ ነበርና ፡ ስለ
ዚህ ፡ ሌዋውያን ፡ ለራሳቸውና ፡ ለአሮን ፡
፲፭ ልጆች ፡ ለካህናቱ ፡ አዘጋጁ ። የአሳፍም ፡
ልጆች ፡ መዘምራን ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፥ እንደ ፡
አሳፍም ፡ እንደ ፡ ኤማንም ፡ የንጉሡም ፡ ባለ ፡
ራእይ ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡ እንደ ፡ ኤዶታም ፡
ትእዛዝ ፡ በየስፍራቸው ፡ ነበሩ ፤ በረኞቹም ፡
በሮቹን ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቁ ፡ ነበር ፤ ወንድሞቻቸ
ውም ፡ ሌዋውያን ፡ ያዘጋጁላቸው ፡ ነበርና ፡ ከአ
ገልግሎታቸው ፡ ይርቁ ፡ ዘንድ ፡ አያስፈልጋቸ
ውም ፡ ነበር ።

፲፮ እንደ ፡ ንጉሡም ፡ እንደ ፡ ኢዮስያስ ፡ ትእ
ዛዝ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ የሚቃ
ጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፥ ፋሲ
ካውንም ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ አገ
፲፯ ልግሎት ፡ ሁሉ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ተዘጋጀ ። የተ
ገኙትም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡
ፋሲካውን ፥ ሰባት ፡ ቀንም ፡ የቂጣ ፡ በዓልን ፡
፲፰ አደረጉ ። ከነቢዩም ፡ ከሳሙኤል ፡ ዘመን ፡
ጀምሮ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ፋሲካ ፡ በእስራኤል ፡
ዘንድ ፡ ከቶ ፡ አልተደረገም ፤ ከእስራኤልም ፡
ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ ኢዮስያስና ፡ ካህናቱ ፥ ሌዋ
ውያኑም ፥ በዚያም ፡ የተገኙ ፡ የይሁዳና ፡ የእ
ስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡
የሚኖሩት ፡ እንዳደረጉት ፡ ያለ ፡ ፋሲካ ፡ ያደረገ ፡
፲፱ የለም ። ይህም ፡ ፋሲካ ፡ ኢዮስያስ ፡ በነገሠ ፡
በአሥራ ፡ ስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ ተደረገ ።

፳ ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ በኋላ ፥ ኢዮስያስም ፡ ቤተ ፡
መቅደሱን ፡ ካሰናዳ ፡ በኋላ ፥ የግብጽ ፡ ንጉሥ ፡
ኒካው ፡ በኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡
በከርከሚሽ ፡ ላይ ፡ ይዋጋ ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ፤ ኢዮ
፳፩ ስያስም ፡ ሊጋጠመው ፡ ወጣ ። እርሱም ፦ የይ
ሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አለኝ?
በምዋጋበት ፡ በሌላ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
በአንተ ፡ ላይ ፡ ዛሬ ፡ አልመጣሁም ፤ እግዚአብ
ሔርም ፡ እንድቸኵል ፡ አዝዞኛል ፤ ከእኔ ፡ ጋር ፡
ያለው ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳያጠፋህ ፡ ይህን ፡
በእርሱ ፡ ላይ ፡ ከማድረግ ፡ ተመለስ ፡ ብሎ ፡ መል
፳፪ እክተኞችን ፡ ላከበት ። ኢዮስያስ ፡ ግን ፡ ይዋ
ጋው ፡ ዘንድ ፡ ተጸናና ፡ እንጂ ፡ ፊቱን ፡ ከእርሱ ፡
አልመለሰም ፤ በእግዚአብሔርም ፡ አፍ ፡ የተነገ
ረውን ፡ የኒካውን ፡ ቃል ፡ አልሰማም ፥ በመጊ
፳፫ ዶም ፡ ሸለቆ ፡ ይዋጋ ፡ ዘንድ ፡ መጣ ። ቀስተኞ
ችም ፡ ንጉሡን ፡ ኢዮስያስን ፡ ወጉት ፤ ንጉ
ሡም ፡ ብላቴኖቹን ፦ አጥብቄ ፡ ቈስያለሁና ፡
፳፬ ከሰልፉ ፡ ውስጥ ፡ አውጡኝ ፡ አላቸው ። ብላ
ቴኖቹም ፡ ከሰረገላው ፡ አውርደው ፡ ለእርሱ ፡
በነበረው ፡ በሁለተኛው ፡ ሰረገላ ፡ ውስጥ ፡ አስ
ቀመጡት ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ አመጡት ፤
እርሱም ፡ ሞተ ፥ በአባቶቹም ፡ መቃብር ፡ ተቀ
በረ ፤ ይሁዳና ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ሁሉ ፡ ለኢዮ
፳፭ ስያስ ፡ አለቀሱ ። ኤርምያስም ፡ ለኢዮስያስ ፡
የልቅሶ ፡ ግጥም ፡ ገጠመለት ፤ እስከ ፡ ዛሬም ፡
ድረስ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ መዘምራን ፡ ሁሉ ፡
በልቅሶ ፡ ግጥማቸው ፡ ስለ ፡ ኢዮስያስ ፡ ይናገሩ ፡
ነበር ፤ ይህም ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ወግ ፡ ሆኖ ፡
፳፮ በልቅሶ ፡ ግጥም ፡ ተጽፎአል ። የቀረውም ፡
የኢዮስያስ ፡ ነገር ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ሕግ ፡
፳፯ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ያደረገው ፡ ቸርነት ፥ የፊተኛ
ውና ፡ የኋለኛውም ፡ ነገሩ ፥ እነሆ ፥ በእስራኤ
ልና ፡ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፎ
አል ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፮ ።

፩ የአገሩም ፡ ሰዎች ፡ የኢዮስያስን ፡ ልጅ ፡ ኢዮ
አክስን ፡ ወስደው ፡ በአባቱ ፡ ፋንታ ፡ በኢየሩሳ
፪ ሌም ፡ አነገሡት ። ኢዮአክስም ፡ መንገሥ ፡ በጀ
መረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡
ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ ነገሠ ።
፫ የግብጽም ፡ ንጉሥ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ከመንግ
ሥቱ ፡ አወጣው ፥ መቶም ፡ መክሊት ፡ ብርና ፡
፬ አንድ ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፡ ዕዳ ፡ ጣለበት ። የግ
ብጽም ፡ ንጉሥ ፡ ወንድሙን ፡ ኤልያቄምን ፡
በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ አነገሠ ፥ ስሙ
ንም ፡ ኢዮአቄም ፡ ብሎ ፡ ለወጠ ፤ ኒካውም ፡
ወንድሙን ፡ ኢዮአክስን ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡
ወሰደው ።

፭ ኢዮአቄምም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡
የሀያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢ
የሩሳሌምም ፡ አሥራ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤
በአምላኩም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡
፮ አደረገ ። የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡
በእርሱ ፡ ላይ ፡ መጥቶ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ይወ
፯ ስደው ፡ ዘንድ ፡ በሰንሰለት ፡ አሰረው ። ናቡ
ከደነፆርም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ዕቃ ፡
አያሌውን ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ አፈለሰ ፥ በባቢ
፰ ሎንም ፡ በመቅደሱ ፡ ውስጥ ፡ አኖረው ። የቀረ
ውም ፡ የኢዮአቄም ፡ ነገር ፥ ያደረገውም ፡ ርኵ
ሰት ፥ በእርሱም ፡ የተገኘው ፡ ሁሉ ፥ እነሆ ፥ በእ
ስራኤልና ፡ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ መጽሐፍ ፡
ተጽፎአል ፤ ልጁም ፡ ዮአኪን ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡
ነገሠ ።

፱ ዮአኪንም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የአ
ሥራ ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢ
የሩሳሌምም ፡ ሦስት ፡ ወርና ፡ አሥር ፡ ቀን ፡

ነገሠ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ። ፲ ዓመቱ ፡ ባለፈ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሡ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ልኮ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ወሰደው ÷ የከበረውንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ዕቃ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አስወሰደ ፤ ወንድሙንም ፡ ሴዴቅያስን ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ አነገሠ ።

፲፩ ሴዴቅያስ ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ÷ በኢየሩሳሌ ፲፪ ምም ፡ አሥራ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ። በአምላኩም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ አፍ ፡ በተናገረው ፡ በነቢዩ ፡ ፲፫ በኤርምያስ ፡ ፊት ፡ ራሱን ፡ አላዋረደም ። ደግሞም ፡ በእግዚአብሔር ፡ አምሎት ፡ በነበረው ፡ በንጉሡ ፡ በናቡከደነፆር ፡ ላይ ፡ ዐመፀ ፤ ወደ ፡ እስራኤልም ፡ አምላክ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳይመለስ ፡ አንገቱን ፡ አደነደነ ፡ ልቡንም ፡ ፲፬ አጠነከረ ። ደግሞም ፡ የካህናቱ ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ሕዝቡም ፡ እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ያለ ፡ ርኵሰት ፡ ሁሉ ፡ መተላለፍን ፡ አበዙ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ የቀደሰውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ፲፭ አረከሱ ። የአባቶቻቸውም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡና ፡ ለማደሪያው ፡ ስላዘነ ፡ ማለዳ ፡ ተነሥቶ ፡ በመልእክተኞቹ ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ ፲፮ እነርሱ ፡ ይልክ ፡ ነበር ። እነርሱ ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ እስኪወጣ ፡ ድረስ ÷ ፈውስም ፡ እስከማይገኝላቸው ፡ ድረስ ÷ በእግዚአብሔር ፡ መልእክተኞች ፡ ይሳለቁ ÷ ቃሉንም ፡ ያቃልሉ ÷ በነቢያቱም ፡ ላይ ፡ ያፌዙ ፡ ነበር ።

፲፯ ስለዚህም ፡ የከለዳውያንን ፡ ንጉሥ ፡ አመጣባቸው ፤ እርሱም ፡ ጕልማሶቻቸውን ፡ በቤተ ፡ መቅደሱ ፡ ውስጥ ፡ በሰይፍ ፡ ገደላቸው ፤ ጕልማሳውንና ፡ ቈንጆይቱን ፡ ሽማግሌውንና ፡ አሮጌውን ፡ አልማረም ፤ ሁሉንም ፡ በእጁ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠው ። ፲፰ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ÷ ታላቁንና ፡ ታናሹን ÷ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ መዝገብ ÷ የንጉሡንና ፡ የአለቆቹን ፡ መዝገብ ÷ እነዚህን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ወሰደ ። ፲፱ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ አቃጠሉ ÷ የኢየሩሳሌምንም ፡ ቅጥር ፡ አፈረሱ ÷ አዳራሾችዋንም ፡ በእሳት ፡ አቃጠሉ ÷ መልካሙንም ፡ ዕቃዋን ፡ ሁሉ ፡ አጠፉ ። ፳ ከሰይፍም ፡ ያመለጡትን ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ማረካቸው ፤ የፋርስ ፡ ንጉሥም ፡ እስኪነግሥ ፡ ድረስ ፡ ለንጉሡና ፡ ለልጆቹ ፡ ባሪያዎች ፡ ሆኑ ፤ ፳፩ በኤርምያስ ፡ አፍ ፡ የተነገረው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንዲፈጸም ÷ ምድሪቱ ፡ ሰንበትን ፡ በማድረግዋ ፡ እስክታርፍ ፡ ድረስ ፤ በተፈታችበትም ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ÷ ሰባ ፡ ዓመት ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ÷ ሰንበትን ፡ አገኘች ።

፳፪ በኤርምያስም ፡ አፍ ፡ የተናገረው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ በፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ በቂሮስ ፡ በመጀመሪያው ፡ ዓመት ፡ እግዚአብሔር ፡ የፋርስን ፡ ንጉሥ ፡ የቂሮስን ፡ መንፈስ ፡ አስነሣ ፤ እርሱም ፡— የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ፳፫ ቂሮስ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የሰማይ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ የምድርን ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ ሰጥቶኛል ፤ በይሁዳም ፡ ባለችው ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ቤት ፡ እሠራለት ፡ ዘንድ ፡ አዝዞኛል ፤ ከሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ማንም ፡ ቢሆን ፡ አምላኩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይሁን ÷ እርሱም ፡ ይውጣ ፡ ብሎ ፡ በመንግሥቱ ፡ ሁሉ ፡ አዋጅ ፡ አስነገረ ÷ ደግሞም ፡ በጽሕፈት ፡ አደረገው ።

# መ ጽ ሐ ፈ ዕ ዝ ራ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ በኤርምያስም ፡ አፍ ፡ የተናገረው ፡ የእግ
ዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ በፋርስ ፡
ንጉሥ ፡ በቂሮስ ፡ በመጀመሪያው ፡ ዓመት ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ የፋርስን ፡ ንጉሥ ፡ የቂሮስን ፡ መን
ፈስ ፡ አስነሣ ፤ እርሱም ፡ በመንግሥቱ ፡ ሁሉ ፡
አዋጅ ፡ አስነገረ ፥ ደግሞም ፡ በጽሕፈት ፡ አድ
፪፤ ርጎ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ቂሮስ ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— የሰማይ ፡ አምላክ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ የምድርን ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡
ሰጥቶኛል ፤ በይሁዳም ፡ ባለችው ፡ በኢየሩ
ሳሌም ፡ ቤት ፡ እሠራለት ፡ ዘንድ ፡ አዝዞኛል ፤
፫፤ ከሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ማንም ፡
ቢሆን ፡ አምላኩ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፥ እር
ሱም ፡ በይሁዳ ፡ ወዳለችው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳ
ሌም ፡ ይውጣ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ለሚኖረው ፡
አምላክ ፥ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብ
፬፤ ሔር ፡ ቤት ፡ ይሥራ ፤ በሚኖርበትም ፡ ስፍራ ፡
ሁሉ ፡ ለቀረው ፡ ሰው ፡ የአገሩ ፡ ሰዎች ፡ በብ
ርና ፡ በወርቅ ፡ በዕቃም ፡ በእንስሳም ፡ ይርዱት ፤
ይህም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላለው ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ ቤት ፡ በፈቃዳቸው ፡ ከሚያቀርቡት ፡
ሌላ ፡ ይሁን ።

፭፤ የይሁዳና ፡ የብንያም ፡ የአባቶች ፡ ቤቶች ፡
አለቆችም ፥ ካህናቱም ፥ ሌዋውያኑም ፥ በኢ
የሩሳሌም ፡ ያለውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡
ለመሥራት ፡ ይወጡ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡
መንፈሳቸውን ፡ ያነሣሣው ፡ ሁሉ ፡ ተነሡ ።
፮፤ በዙሪያቸውም ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ በፈቃዳቸው ፡
ካቀረቡት ፡ ሁሉ ፡ ሌላ ፡ በብር ፡ ዕቃና ፡ በወርቅ ፡
በገንዘቦችና ፡ በእንስሶች ፡ በሌላም ፡ ስጦታ ፡
፯፤ አገዙአቸው ። ንጉሡ ፡ ቂሮስም ፡ ናቡከደነ
ፆር ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ወስዶ ፡ በአማልክቱ ፡
ቤት ፡ ያኖራቸውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡
፰፤ ዕቃዎች ፡ አወጣ ። የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ቂሮስም ፡
በመዝገቡ ፡ ላይ ፡ በነበረው ፡ በሚትሪዳጡ ፡
እጅ ፡ አወጣቸው ፥ ለይሁዳም ፡ መስፍን ፡ ለሰሳ
፱፤ ብሳር ፡ ቈጠራቸው ። ቍጥራቸውም ፡ ይህ ፡
ነው ፤ ሠላሳ ፡ የወርቅ ፡ አንድ ፡ ሺህም ፡
የብር ፡ ሰሐኖች ፥ ሀያ ፡ ዘጠኝም ፡ ቢላዎች ፥
፲፤ ሠላሳ ፡ የወርቅ ፡ ደከሞች ፥ አራት ፡ መቶ ፡
አሥርም ፡ ሌላ ፡ ዓይነት ፡ የብር ፡ ደከሞች ፥
፲፩፤ አንድ ፡ ሺህም ፡ ሌላ ፡ ዕቃ ፡ ነበረ ። የወር
ቁና ፡ የብሩ ፡ ዕቃዎች ፡ ሁሉ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡
አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ፤ እነዚህንም ፡ ሁሉ ፡
ሰሳብሳር ፡ ከባቢሎን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ከተ
መለሱ ፡ ምርኮኞቹ ፡ ጋር ፡ ወሰደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፤ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ወደ ፡
ባቢሎን ፡ ከማረካቸው ፡ ምርኮኞች ፡ ወደ ፡ ኢየ
ሩሳሌምና ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ወደ ፡ እየከተማቸው ፡
የተመለሱት ፡ የአገር ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።
፪፤ ከዘሩባቤል ፥ ከኢያሱ ፥ ከነህምያ ፥ ከሠራያ ፥
ከረዕላያ ፥ ከመርዶክዮስ ፥ ከበላሳን ፥ ከመሴ
ፋር ፥ ከበጉዋይ ፥ ከሬሁም ፥ ከበዓና ፡ ጋር ፡
መጡ ።

የእስራኤልም ፡ ሕዝብ ፡ ሰዎች ፡ ቍጥር ፡ ይህ ፡
፫፤ ነው ፤ የፋሮስ ፡ ልጆች ፥ ሁለት ፡ ሺህ ፡ መቶ ፡
፬፤ ሰባ ፡ ሁለት ። የሰፋጥያስ ፡ ልጆች ፥ ሦስት ፡
፭፤ መቶ ፡ ሰባ ፡ ሁለት ። የኤራ ፡ ልጆች ፥ ሰባት ፡
፮፤ መቶ ፡ ሰባ ፡ አምስት ። ከኢያሱና ፡ ከኢዮአብ ፡
ልጆች ፡ የሆኑ ፡ የፈሐት ፡ ሞዓብ ፡ ልጆች ፥
ሁለት ፡ ሺህ ፡ ስምንት ፡ መቶ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ።
፯፤ የኤላም ፡ ልጆች ፥ ሺህ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡
፰፤ አራት ። የዛቱዕ ፡ ልጆች ፥ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ አርባ ፡
፱፤ አምስት ። የዘካይ ፡ ልጆች ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ።
፲፤ የባኒ ፡ ልጆች ፥ ስድስት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ ሁለት ።
፲፩፤ የቤባይ ፡ ልጆች ፥ ስድስት ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሦስት ።
፲፪፤ የዓዝጋድ ፡ ልጆች ፥ ሺህ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡
፲፫፤ ሁለት ። የአዶኒቃም ፡ ልጆች ፥ ስድስት ፡ መቶ ፡
፲፬፤ ስድሳ ፡ ስድስት ። የበጉዋይ ፡ ልጆች ፥ ሁለት ፡
፲፭፤ ሺህ ፡ አምሳ ፡ ስድስት ። የዓዲን ፡ ልጆች ፥
፲፮፤ አራት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ አራት ። ከሕዝቅያስ ፡
ወገን ፡ የአጤር ፡ ልጆች ፥ ዘጠና ፡ ስምንት ።
፲፯፤ የቤሳይ ፡ ልጆች ፥ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሦስት ።
፲፰፤ የዮራ ፡ ልጆች ፥ መቶ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ።
፲፱፤ የሐሱም ፡ ልጆች ፥ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሦስት ።
፳፤ የጋቤር ፡ ልጆች ፥ ዘጠና ፡ አምስት ። ፳፩፤ የቤተ ፡
ልሔም ፡ ልጆች ፥ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሦስት ። የነጦፋ ፡
፳፪፤ ሰዎች ፥ አምሳ ፡ ስድስት ። ፳፫፤ የዓናቶት ፡ ሰዎች ፥
መቶ ፡ ሀያ ፡ ስምንት ። ፳፬፤ የዓዝሞት ፡ ልጆች ፥
አርባ ፡ ሁለት ። ፳፭፤ የቂርያትይዓሪምና ፡ የከፊራ ፡
የብኤሮትም ፡ ልጆች ፥ ሰባት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡
ሦስት ። ፳፮፤ የራማና ፡ የጌባ ፡ ልጆች ፥ ስድስት ፡
መቶ ፡ ሀያ ፡ አንድ ። ፳፯፤ የማክማስ ፡ ሰዎች ፥ መቶ ፡
ሀያ ፡ ሁለት ። ፳፰፤ የቤቴልና ፡ የጋይ ፡ ሰዎች ፥ ሁለት ፡
መቶ ፡ ሀያ ፡ ሦስት ። ፳፱፤ የናባው ፡ ልጆች ፥ አምሳ ፡
ሁለት ። ፴፤ የመጌብስ ፡ ልጆች ፥ መቶ ፡ አምሳ ፡
ስድስት ። ፴፩፤ የሁለተኛውም ፡ ኤላም ፡ ልጆች ፥
ሺህ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ አራት ። ፴፪፤ የካሪም ፡
ልጆች ፥ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሀያ ። ፴፫፤ የሎድና ፡ የሐ
ዲድ ፡ የአኖም ፡ ልጆች ፥ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡
አምስት ። ፴፬፤ የኢያሪኮ ፡ ልጆች ፥ ሦስት ፡ መቶ ፡
አርባ ፡ አምስት ። ፴፭፤ የሴናዓ ፡ ልጆች ፥ ሦስት ፡

ሺህ፡ስድስት፡መቶ፡ሠላሳ።
፴፮፤ ካህናቱ፤ ከኢያሱ፡ወገን፡የዮዳኤ፡ልጆች፥
፴፯፤ ዘጠኝ፡መቶ፡ሰባ፡ሦስት። የኢሜር፡ልጆች፥
፴፰፤ ሺህ፡አምሳ፡ሁለት። የፋስኮር፡ልጆች፥ ሺህ፡
፴፱፤ ሁለት፡መቶ፡አርባ፡ሰባት። የካሪም፡ልጆች፥
ሺህ፡አሥራ፡ሰባት።
፵፤ ሌዋውያኑ፤ ከሆዳይዋ፡ወገን፡የኢያሱና፡
የቀድምኤል፡ልጆች፥ሰባ፡አራት።
፵፩፤ መዘምራኑ፤ የአሳፍ፡ልጆች፥ መቶ፡ሀያ፡
ስምንት።
፵፪፤ የበረኞች፡ልጆች፤ የሰሎም፡ልጆች፥የአ
ጤር፡ልጆች፥የጤልሞን፡ልጆች፥የዓቁብ፡
ልጆች፥የሐጢጣ፡ልጆች፥የሰባይ፡ልጆች፥
ሁሉ፡መቶ፡ሠላሳ፡ዘጠኝ።
፵፫፤ ናታኒም፤የሲሐ፡ልጆች፥የሐሡፋ፡ልጆች፥
፵፬፤ የጠብዖት፡ልጆች፥የኬራስ፡ልጆች፥የሲዓ፡
፵፭፤ ልጆች፥የፋዶን፡ልጆች፥የልባና፡ልጆች፥
፵፮፤ የአጋበ፡ልጆች፥የዓቁብ፡ልጆች፥የአጋብ፡
ልጆች፥የሰምላይ፡ልጆች፥የሐናን፡ልጆች፥
፵፯፤ የጌዴል፡ልጆች፥የጋሐር፡ልጆች፥የራያ፡
፵፰፤ ልጆች፥የረአሶን፡ልጆች፥የኔቆዳ፡ልጆች፥
፵፱፤ የጋሴም፡ልጆች፥የዖዛ፡ልጆች፥የፋሴሐ፡
፶፤ ልጆች፥የቤሳይ፡ልጆች፥የአስና፡ልጆች፥
የምዑናውያን፡ልጆች፥የንፉሰሲም፡ልጆች፥
፶፩፤ የበቅቡቅ፡ልጆች፥የሐቁፋ፡ልጆች፥የሐር
፶፪፤ ሑር፡ልጆች፥የበስሎት፡ልጆች፥የምሒዳ፡
፶፫፤ ልጆች፥የሐርሳ፡ልጆች፥የበርቆስ፡ልጆች፥
፶፬፤ የሲሣራ፡ልጆች፥የቴማ፡ልጆች፥የንስያ፡
ልጆች፥የሐጢፋ፡ልጆች።
፶፭፤ የሰሎሞንም፡ባሪያዎች፡ልጆች፤ የሶጣይ፡
ልጆች፥የሶፌሬት፡ልጆች፥የፍሩዳ፡ልጆች፥
፶፮፤ የየዕላ፡ልጆች፥የደርቆን፡ልጆች፥የጌዴል፡
፶፯፤ ልጆች፥ የሰፋጥያስ፡ልጆች፥ የሐጢል፡
ልጆች፥የፈክራት፡ልጆች፥የሐዊበይም፡
፶፰፤ ልጆች፥የአሚ፡ልጆች። እነዚህ፡ናታኒም፡
ሁሉና፡የሰሎሞን፡ባሪያዎች፡ልጆች፡ሦስት፡
መቶ፡ዘጠና፡ሁለት፡ነበሩ።
፶፱፤ ከቴልሜላ፥ከቴላሬሳ፥ከክሩብ፥ከአዳን፥
ከኢሜር፡የወጡ፡እነዚህ፡ነበሩ፤ ነገር፡ግን፡
የአባቶቻቸውን፡ቤቶችና፡ዘራቸውን፡ወይም፡
ከእስራኤል፡ወገን፡መሆናቸውን፡ያስታውቁ፡
፷፤ ዘንድ፡አልቻሉም፤ የዳላያ፡ልጆች፥የጦ
ብያ፡ልጆች፥የኔቆዳ፡ልጆች፥ስድስት፡
፷፩፤ መቶ፡አምሳ፡ሁለት፡ነበሩ። ከካህናቱም፡
ልጆች፤የኤብያ፡ልጆች፥የአቆስ፡ልጆች፥
ከገለዓዳዊው፡ከቤርዜሊ፡ልጆች፡ሚስት፡
ያገባ፥በስሙም፡የተጠራ፡የቤርዜሊ፡ልጆች።
፷፪፤ እነዚህ፡በትውልድ፡መጽሐፍ፡ትውልዳቸ
ውን፡ፈለጉ፤ ነገር፡ግን፡አልተገኘም፥ ከክ
፷፫፤ ህነትም፡ተከለከሉ። ሐቴርሰታም፡— በኡሪ
ምና፡በቱሚም፡የሚፈርድ፡ካህን፡እስኪነሣ፡
ድረስ፡ከቅዱሰ፡ቅዱሳን፡አትበሉም፡አላ
ቸው።
፷፬፡፷፭፤ ሰባት፡ሺህ፡ሦስት፡መቶ፡ሠላሳ፡ሰባት፡
ከነበሩ፡ከሎሌዎቻቸውና፡ከገረዶቻቸው፡ሌላ፡
ጉባኤው፡ሁሉ፡አርባ፡ሁለት፡ሺህ፡ሦስት፡
መቶ፡ስድሳ፡ነበሩ። ሁለት፡መቶም፡ወንዶ
፷፮፤ ችና፡ሴቶች፡መዘምራን፡ነበሩአቸው። ፈረሶ
ቻቸውም፡ሰባት፡መቶ፡ሠላሳ፡ስድስት፥
በቅሎቻቸውም፡ሁለት፡መቶ፡አርባ፡አም
፷፯፤ ስት፥ግመሎቻቸውም፡አራት፡መቶ፡ሠላሳ፡
አምስት፥ አህዮቻቸውም፡ስድስት፡ሺህ፡
ሰባት፡መቶ፡ሀያ፡ነበሩ።
፷፰፤ በኢየሩሳሌምም፡ወዳለው፡ወደ፡እግዚአብ
ሔር፡ቤት፡በመጡ፡ጊዜ፡ከአባቶች፡ቤቶች፡
አለቆች፡አያሌዎች፡ለእግዚአብሔር፡ቤት፡
በስፍራው፡ይሠራ፡ዘንድ፡በፈቃዳቸው፡
፷፱፤ ሰጡ። ስድሳ፡አንድ፡ሺህም፡የወርቅ፡ዳሪክ፥
አምስት፡ሺህም፡ምናን፡ብር፥ አንድ፡
መቶም፡የካህናት፡ልብስ፡እንደ፡ችሎታቸው፡
ወደ፡ሥራው፡ቤት፡መዛግብት፡አቀረቡ።
፸፤ ካህናቱና፡ሌዋውያኑም፥ከሕዝቡም፡አያ
ሌዎች፥መዘምራኑና፡በረኞቹም፥ናታኒምም፡
በከተሞቻቸው፥እስራኤልም፡ሁሉ፡በከተ
ሞቻቸው፡ተቀመጡ።

## ምዕራፍ፡፫።

፩፤ ሰባተኛውም፡ወር፡በደረሰ፡ጊዜ፥የእስራ
ኤልም፡ልጆች፡በከተሞቻቸው፡ሳሉ፥ሕዝቡ፡
እንደ፡አንድ፡ሰው፡ሆነው፡ወደ፡ኢየሩሳ
፪፤ ሌም፡ተሰበሰቡ። የኢዮሴዴቅም፡ልጅ፡
ኢያሱ፥ወንድሞቹም፡ካህናቱ፥የሰላትያልም፡
ልጅ፡ዘሩባቤል፡ወንድሞቹም፡ተነሥተው፡
በእግዚአብሔር፡ሰው፡በሙሴ፡ሕግ፡እንደ፡
ተጻፈ፡የሚቃጠለውን፡መሥዋዕት፡ያቀር
ቡበት፡ዘንድ፡የእስራኤልን፡አምላክ፡መሠ
፫፤ ዊያ፡ሠሩ። በአገሩም፡ካሉት፡አሕዛብ፡ፈር
ተው፡ነበርና፡መሠዊያውን፡በስፍራው፡ላይ፡
አስቀመጡት፥በጥዋትና፡በማታም፡የሚቃጠ
ለውን፡መሥዋዕት፡ለእግዚአብሔር፡አቀረቡ
፬፤ በት። እንደ፡ተጻፈውም፡የዳስ፡በዓል፡አደረጉ፤
እንደ፡ሥርዓቱም፡ለየዕለቱ፡የተገባውን፡የየ
ዕለቱን፡የሚቃጠል፡መሥዋዕት፡በቍጥር፡አቀ
፭፤ ረቡ። ከዚያም፡በኋላ፡ዘወትር፡የሚቃጠለውን፡
መሥዋዕት፥የመባቻውንም፡መሥዋዕት፥የተ
ቀደሱትንም፡የእግዚአብሔር፡በዓላት፡ሁሉ፡
መሥዋዕት፥ሰውም፡ሁሉ፡ለእግዚአብሔር፡
በፈቃድ፡የሰጠውን፡ቍርባን፡አቀረቡ።
፮፤ በሰባተኛው፡ወር፡በመጀመሪያው፡ቀን፡ለእ
ግዚአብሔር፡የሚቃጠል፡መሥዋዕት፡ማቅ
ረብ፡ጀመሩ፤ የእግዚአብሔር፡መቅደስ፡ገና፡
፯፤ አልተመሠረተም፡ነበር። ለጠራቢዎችና፡ለአ
ናጢዎችም፡ገንዘብ፡ሰጡ፤የፋርስም፡ንጉሥ፡
ቂሮስ፡እንደ፡ፈቀደላቸው፡የዝግባ፡ዛፍ፡
ከሊባኖስ፡በባሕር፡ወደ፡ኢዮጴ፡ያመጡ፡
ዘንድ፡ለሲዶናና፡ለጢሮስ፡ሰዎች፡መብልና፡
መጠጥ፡ዘይትም፡ሰጡ።
፰፤ በኢየሩሳሌም፡ወዳለው፡ወደ፡እግዚአብ

ሔር ፡ ቤት ፡ በመጡ ፡ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡
በሁለተኛውም ፡ ወር ፡ የሰላትያል ፡ ልጅ ፡ ዘሩ
ባቤል ÷ የኢዮሴዴቅም ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ÷ የቀሩ
ትም ፡ ወንድሞቻቸው ፡ ካህናትና ፡ ሌዋውያን ÷
ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ የተመለሱት ፡ ምርኮ
ኞች ፡ ሁሉ ፡ ጀመሩ ፤ ሌዋውያንንም ፡ ከሀያ ፡
ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ቤት ፡ ሥራ ፡ እንዲያሠሩት ፡ ሾሙአ
፱ ቸው ። ኢያሱም ፡ ልጆቹም ፡ ወንድሞቹም ÷ የይ
ሁዳም ፡ ልጆች ፡ ቀድምኤልና ፡ ልጆቹ ÷ የኤ
ንሐዳድም ፡ ልጆች ÷ ልጆቻቸውና ፡ ወንድሞ
ቻቸው ፡ ሌዋውያንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡
የሚሠሩትን ፡ ያሠሩ ፡ ዘንድ ፡ በአንድነት ፡
፲ ቆሙ ። አናጢዎቹም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መቅ
ደስ ፡ በመሠረቱ ፡ ጊዜ ፡ ካህናቱ ፡ ልብሳቸውን ፡
ለብሰው ፡ መለከቱን ፡ ይዘው ÷ የአሳፍም ፡
ልጆች ፡ ሌዋውያን ፡ ጸናጽል ፡ ይዘው ፡ እንደ ፡
እስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፡ ሥርዓት ፡
እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ፡ ቆሙ ።
፲፩ ደግሞ ፡— ቸር ፡ ነውና ÷ ለእስራኤልም ፡ ምሕ
ረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፡ እያሉ ፡ እግዚአብሔ
ንም ፡ እያመሰገኑና ፡ እያከበሩ ፡ እርስ ፡ በእርሳ
ቸው ፡ ያስተዛዝሉ ፡ ነበር ፤ የእግዚአብሔርም ፡
ቤት ፡ ስለ ፡ ተመሠረተ ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ እያመሰገኑ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ እልል ፡
፲፪ አሉ ። የፊተኛውን ፡ ቤት ፡ ያዩ ፡ ሽማግሌዎች ፡
የሆኑ ፡ ብዙ ፡ ካህናትና ፡ ሌዋውያን ፡ የአባቶችም ፡
ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ግን ፡ ይህ ፡ መቅደስ ፡ በፊታ
ቸው ፡ በተመሠረተ ፡ ጊዜ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡
ያለቅሱ ፡ ነበር ፤ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ በደስታ ፡
፲፫ ይጮኹ ፡ ነበር ፤ ደስ ፡ ብሎአቸው ፡ የሚጮ
ኹትን ፡ ድምፅ ፡ ከሕዝቡ ፡ ልቅሶ ፡ ድምፅ ፡
መለየት ፡ የሚችል ፡ አልነበረም ፤ ሕዝቡም ፡
በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ይጮኹ ፡ ነበር ÷ ድምፁም ፡
ከሩቅ ፡ ይሰማ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ የይሁዳና ፡ የብንያምም ፡ ጠላቶች ፡ ምርኮ
ኞቹ ፡ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
፪ መቅደስ ፡ እንደ ፡ ሠሩ ፡ ሰሙ ። ወደ ፡ ዘሩባቤ
ልና ፡ ወደ ፡ አባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ቀር
በው ፡— የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ አስራዶን ፡ ወደዚህ ፡
ካመጣን ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ ለአምላካችሁ ፡ እንሠ
ዋለንና ÷ እንደ ፡ እናንተም ፡ እንፈልገዋለንና ፡
፫ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እንሥራ ፡ አሉአቸው ። ዘሩባ
ቤልና ፡ ኢያሱም ፡ የቀሩትም ፡ የእስራኤል ፡
አባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡— የአምላካችንን ፡
ቤት ፡ መሥራት ፡ ለእኛና ፡ ለእናንተ ፡ አይደ
ለም ፤ እኛ ፡ ለብቻችን ፡ ግን ፡ የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡
ቂሮስ ፡ እንዳዘዘን ፡ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እንሠራለን ፡ አሉአቸው ።
፬ የምድሩም ፡ ሕዝብ ፡ የይሁዳን ፡ ሕዝብ ፡ እጅ ፡
ያደክሙ ፡ ነበር ÷ እንዳይሠሩም ፡ አስፈራሩአ
፭ ቸው ÷ ምክራቸውንም ፡ ያፈርሱ ፡ ዘንድ ፡ በፋ
ርሱ ፡ ንጉሥ ፡ በቂሮስ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡
ፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ እስከ ፡ ዳርዮስ ፡ መንግሥት ፡
፮ ድረስ ፡ መካሪዎችን ፡ ገዙባቸው ። በአርጤክ
ስስም ፡ መንግሥት ÷ በመንግሥቱም ፡ በመጀ
መሪያ ፡ ዘመን ÷ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡
በሚኖሩት ፡ ላይ ፡ የክስ ፡ ነገር ፡ ጻፉ ።

፯ በአርጤክስስም ፡ ዘመን ፡ ቢሽላም ÷ ሚትሪ
ዳጡ ÷ ጣብኤል ፡ ተባባሪዎቹም ፡ ለፋርስ ፡
ንጉሥ ፡ ለአርጤክስስ ፡ ጻፉ ፤ ደብዳቤውም ፡
በሶርያ ፡ ፊደልና ፡ በሶርያ ፡ ቋንቋ ፡ ተጽፎ ፡
፰ ነበር ። አዛገፉ ፡ ሬሁም ፡ ጸሐፊውም ፡ ሲምሳይ ፡
በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ ለንጉሡ ፡ ለአርጤክስስ ፡
፱ እንዲህ ፡ የሚል ፡ ደብዳቤ ፡ ጻፉ ። አዛገፉ ፡
ሬሁም ፡ ጸሐፊውም ፡ ሲምሳይ ፡ የቀሩትም ፡
ተባባሪዎቻቸው ÷ ዲናውያን ÷ አፈርሳትካው
ያን ÷ ጠርፈላውያን ÷ አፈርሳውያን ÷ አርካው
ያን ÷ ባቢሎናውያን ÷ ሱስናካውያን ÷ ዴሐው
፲ ያን ÷ ኤላማውያን ÷ ታላቁና ፡ ኃይለኛው ፡ አስ
ናፈር ፡ ያፈለሳቸው ፡ በሰማርያና ፡ በወንዝ ፡
ማዶ ፡ ያኖራቸው ፡ የቀሩትም ፡ አሕዛብ ፡ ደብዳ
ቤውን ፡ ጻፉ ።

፲፩ ለንጉሡ ፡ ለአርጤክስስ ፡ የላኩት ፡ የደብዳቤ ፡
ግልባጭ ፡ ይህ ፡ ነው ፡— በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ያሉት ፡
፲፪ ሰዎች ፡ ባሪያዎችህ ፤ አሁንም ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡
የወጡ ፡ አይሁድ ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳ
ሌም ፡ እንደ ፡ መጡ ፡ ንጉሡ ፡ ይወቅ ፤ ዓመፀኛ
ይቱንና ፡ እጅግም ፡ የከፋችቱን ፡ ከተማ ፡ ይሠ
ራሉ ÷ ቅጥርዋንም ፡ ያድሳሉ ÷ መሠረትዋንም ፡
፲፫ ጠገኑ ። አሁንም ፡ ይህች ፡ ከተማ ፡ የተሠራች ፡
እንደ ፡ ሆነ ÷ ቅጥርዋም ፡ የታደሰ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷
ግብርና ፡ ቀረጥ ፡ መጥንም ፡ እንዳይሰጡ ÷ የን
ጉሡም ፡ ግቢው ፡ እንዲጎድል ፡ ንጉሡ ፡ ይወቅ ።
፲፬ የንጉሡንም ፡ ጨው ፡ እንበላለንና ÷ ንጉሡ
ንም ፡ ሲያቃልሉት ፡ ማየት ፡ አይገባንምና ፡ ስለ
፲፭ ዚህ ፡ ልከን ፡ ለንጉሡ ፡ አስታውቀናል ፤ በአባ
ቶችህ ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ምርመራ ፡ ይደረግ ፤
በዚያም ፡ በታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ይህች ፡ ከተማ ፡
ዓመፀኛ ፡ እንደ ፡ ሆነች ÷ ነገሥታትንና ፡ አው
ራጃዎችንም ፡ እንደ ፡ ጎዳች ÷ ከጥንቱም ፡ ሽፍ
ትነት ፡ በእርስዋ ፡ እንደ ፡ ተጀመረ ፡ ታገኛለህ ÷
ታውቃለህም ፤ ስለዚህም ፡ ይህች ፡ ከተማ ፡
፲፮ ፈርሳ ፡ ነበር ። ይህችም ፡ ከተማ ፡ የተሠራች ፡
እንደ ፡ ሆነ ÷ ቅጥርዋም ፡ የታደሰ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷
በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ክፍል ፡ እንደሌለህ ፡ ለንጉሡ ፡
እናስታውቃለን ።

፲፯ ንጉሡም ፡ ለአዛገፉ ፡ ለሬሁም ÷ ለጸሐፊ
ውም ፡ ለሲምሳይ ÷ በሰማርያና ፡ በወንዝ ፡
ማዶም ፡ ለተቀመጡ ፡ ለቀሩት ፡ ተባባሪዎቻ
ቸው ፡ እንዲህ ፡ የሚለውን ፡ መልስ ፡ ላከ ፡—
፲፰ ሰላም ፤ አሁንም ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ የላካችሁት ፡
፲፱ ደብዳቤ ፡ በፊቴ ፡ ተተርጕሞ ፡ ተነበበ ። እኔም ፡
አዝዤለሁ ÷ ተመረመረም ፤ ይህችም ፡ ከተማ ፡
ከጥንት ፡ ጀምራ ፡ በነገሥታት ፡ ላይ ፡ ዓመፀኛ ፡
እንደ ፡ ነበረች ÷ በእርስዋም ፡ ዓመፅና ፡ ሽፍ

፳ ትንት ፡ እንደ ፡ ተደረገ ፡ ተገኘ ። በኢየሩሳሌ
ምም ፡ እጅግ ፡ ኃያላን ፡ ነገሥታት ፡ ነበሩ ፥ በወ
ንዝም ፡ ማዶ ፡ ያለውን ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ይገዙ ፡
ነበር ፤ ግብርንና ፡ ቀረጥን ፡ መጥንንም ፡ ይቀ
፳፩ በሉ ፡ ነበር ። አሁንም ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ሥራ
ውን ፡ እንዲተዉ ፥ እኔም ፡ እስካዝዝ ፡ ድረስ ፡
ይህች ፡ ከተማ ፡ እንዳትሠራ ፡ ትእዛዝ ፡ ስጡ ።
፳፪ ቸልም ፡ እንዳትሉ ፡ ተጠንቀቁ ፤ ለነገሥታቱ ፡
ጉዳትና ፡ ጥፋት ፡ እየበዛ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይሄዳል ?
፳፫ የንጉሡም ፡ የአርጤክስስ ፡ ደብዳቤ ፡ ግል
ባጭ ፡ በሬሁምና ፡ በጸሐፊው ፡ በሲምሳይ ፡
በተባባሪዎቻቸውም ፡ ፊት ፡ በተነበበ ፡ ጊዜ ፡
ፈጥነው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ አይሁድ ፡
ሄዱ ፤ በግድና ፡ በኃይልም ፡ አስተዉአቸው ።
፳፬ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያለው ፡ የእ
ግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ሥራ ፡ ቀረ ፤ እስከ ፡ ፋር
ስም ፡ ንጉሥ ፡ እስከ ፡ ዳርዮስ ፡ መንግሥት ፡
እስከ ፡ ሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ተጓጐለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ነቢያቱም ፡ ሐጌና ፡ የአዶ ፡ ልጅ ፡ ዘካርያስ ፡
በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለነበሩ ፡ አይሁድ ፡
በእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ስም ፡ ትንቢት ፡ ተና
፪ ገሩላቸው ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ የሰላትያል ፡
ልጅ ፡ ዘሩባቤል ፡ የኢዮሴዴቅም ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡
ተነሥተው ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያለውን ፡ የእግዚ
አብሔርን ፡ ቤት ፡ መሥራት ፡ጀመሩ ፤ የሚያ
ግዙአቸውም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነቢያት ፡ ከእ
፫ ነርሱ ፡ ጋር ፡ ነበሩ ። በዚያም ፡ ዘመን ፡ በወ
ንዝ ፡ ማዶ ፡ የነበረው ፡ ገዥ ፡ ተንትናይ ፥ ደግሞ ፡
ሰተርቡዝናይ ፥ ተባባሪዎቻቸውም ፡ ወደ ፡
እነርሱ ፡ መጥተው ፡— ይህን ፡ ቤት ፡ ትሠሩ ፡
ዘንድ ፥ ይህንኑም ፡ ቅጥር ፡ ታድሱ ፡ ዘንድ ፡
፬ ያዘዛችሁ ፡ ማን ፡ ነው ? አሉአቸው ። ደግሞም ፡—
ይህንስ ፡ ሥራ ፡ የሚሠሩት ፡ ሰዎች ፡ ስም ፡
፭ ማን ፡ ነው ? ብለው ፡ ጠየቁአቸው ። የአምላካ
ቸው ፡ ዓይን ፡ ግን ፡ በአይሁድ ፡ ሽማግሌዎች ፡
ላይ ፡ ነበረ ፥ ይህም ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ዳርዮስ ፡
እስኪደርስ ፡ ድረስ ፥ መልሱም ፡ በደብዳቤ ፡
እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ አልከለከሉአቸውም ።
፮ በወንዙ ፡ ማዶ ፡ የነበረው ፡ ገዥ ፡ ተንትናይ ፡
ደግሞ ፡ ሰተርቡዝናይ ፡ ተባባሪዎቹም ፡ በወ
ንዙ ፡ ማዶ ፡ የነበሩት ፡ አፈርስካውያን ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ዳርዮስ ፡ የላኩት ፡ የደብዳቤው ፡
፯ ግልባጭ ፡ ይህ ፡ ነበረ ። እንዲህም ፡ የሚል ፡
ደብዳቤ ፡ ላኩለት ፡— ለንጉሡ ፡ ለዳርዮስ ፡
፰ ሙሉ ፡ ሰላም ፡ ይሁን ፤ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ አገር ፡
ወደ ፡ ታላቁም ፡ አምላክ ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ሄድን ፡
ንጉሡ ፡ ይወቅ ፤ እርሱም ፡ በትልቅ ፡ ድን
ጋይ ፡ ተሠራ ፥ በቅጥሩም ፡ ውስጥ ፡ እንጨት ፡
ተደረገ ፥ ያም ፡ ሥራ ፡ በትጋት ፡ ይሠራል ፥
፱ በእጃቸውም ፡ ይከናወናል ። እነዚያንም ፡ ሽማ
ግሌዎች ፡— ይህን ፡ ቤት ፡ ትሠሩ ፡ ዘንድ ፥ ይህ
ንስ ፡ ቅጥር ፡ ታድሱ ፡ ዘንድ ፡ ያዘዛችሁ ፡ ማን ፡
፲ ነው ? ብለን ፡ ጠየቅናቸው ። ደግሞም ፡ እናስ
ታውቅህ ፡ ዘንድ ፥ በእነርሱም ፡ ያሉትን ፡
ሹሞች ፡ ስም ፡ እንጽፍልህ ፡ ዘንድ ፡ ስማቸውን ፡
፲፩ ጠየቅን ። እንደዚህም ፡ ብለው ፡ መለሱልን ፡—
እኛ ፡ የሰማይና ፡ የምድር ፡ አምላክ ፡ ባሪያዎች ፡
ነን ፥ ከብዙም ፡ ዘመን ፡ጀምሮ ፡ ተሠርቶ ፡ የነ
በረውን ፥ ታላቁም ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡
፲፪ ሠርቶ ፡ የፈጸመውን ፡ ቤት ፡ እንሠራለን ። አባቶ
ቻችንም ፡ የሰማይን ፡ አምላክ ፡ ካስቈጡ ፡ በኋላ ፡
በከለዳዊው ፡ በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ በናቡከደነ
ፆር ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፥ እርሱም ፡
ይህን ፡ ቤት ፡ አፈረሰ ፥ ሕዝቡንም ፡ ወደ ፡ ባቢ
፲፫ ሎን ፡ አፈለሰ ። ነገር ፡ ግን ፡ በባቢሎን ፡
ንጉሥ ፡ በቂሮስ ፡ በመጀመሪያው ፡ ዓመት ፡
ንጉሡ ፡ ቂሮስ ፡ ይህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡
፲፬ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ። ናቡከደነፆርም ፡ በኢየ
ሩሳሌም ፡ ከነበረው ፡ መቅደስ ፡ የወሰደውን ፥
ወደ ፡ ባቢሎንም ፡ መቅደስ ፡ ያፈለሰውን ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ የወርቅንና ፡ የብርን ፡
ዕቃ ፡ ንጉሡ ፡ ቂሮስ ፡ ከባቢሎን ፡ መቅደስ ፡
አውጥቶ ፡ ሰሳብሳር ፡ ለተባለው ፡ ለሹሙ ፡
፲፭ ሰጠውና ፡— ይህን ፡ ዕቃ ፡ ይዘህ ፡ ሂድ ፥ በኢ
የሩሳሌምም ፡ ባለው ፡ መቅደስ ፡ አኑረው ፤ የእ
ግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ በስፍራው ፡ ይሠራ ፡
፲፮ አለው ። በዚያ ፡ ጊዜም ፡ ይህ ፡ ሰሳብሳር ፡
መጣ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ያለውን ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ቤት ፡ መሠረተ ፤ ከዚያም ፡ ጊዜ ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እየተሠራ ፡ አል
፲፯ ተጨረሰም ። አሁንም ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ በን
ጉሡ ፡ ዓይን ፡ መልካም ፡ ቢሆን ፡ ይህ ፡ የእግ
ዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ይሠራ ፡
ዘንድ ፡ ከንጉሡ ፡ ከቂሮስ ፡ ታዝዞ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
በባቢሎን ፡ ባለው ፡ በንጉሡ ፡ ቤተ ፡ መዛግብት ፡
ይመርመር ፤ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ንጉሡ ፡ ፈቃ
ዱን ፡ ይላክልን ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ በዚያ ፡ ጊዜም ፡ ንጉሡ ፡ ዳርዮስ ፡ መዛግ
ብት ፡ ባሉበት ፡ በባቢሎን ፡ ቤተ ፡ መጻሕፍት ፡
፪ እንዲመረመር ፡ አዘዘ ። በሜዶን ፡ አውራጃ ፡
ባለው ፡ አሕምታ ፡ በሚባል ፡ ከተማ ፡ በንጉሡ ፡
ቤት ፡ ውስጥ ፡ አንድ ፡ ጥቅልል ፡ ተገኘ ፥ በው
ስጡም ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ለመታሰቢያ ፡ ተጽፎ ፡
፫ ነበር ። በንጉሡ ፡ በቂሮስ ፡ በመጀመሪያው ፡
ዓመት ፡ ንጉሡ ፡ ቂሮስ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘዘ ፤
በኢየሩሳሌም ፡ ያለው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፥
መሥዋዕት ፡ የሚቀርብበት ፡ ቦታ ፥ ይህ ፡ ቤት ፡
ይሠራ ፥ በጽኑም ፡ ይመሥረት ፤ ቁመቱ ፡ ስድሳ ፡
ክንድ ፡ ወርዱም ፡ ስድሳ ፡ ክንድ ፡ ይሁን ።
፬ በሦስት ፡ ተራ ፡ ታላላቅ ፡ ድንጋይ ፥ በአንድ ፡
ተራ ፡ እንጨት ፡ ይደረግ ፤ ወጪውም ፡ ከን
፭ ጉሡ ፡ ቤት ፡ ይሰጥ ። ናቡከደነፆርም ፡ በኢየ
ሩሳሌም ፡ ካለው ፡ መቅደስ ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ ባቢ
ሎን ፡ ያመጣው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የወ

ርቅና ፡ የብር ፡ ዕቃ ፡ ይመለስ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡
ወዳለው ፡ መቅደስ ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ይወሰድ ÷
በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ይኑር ።
፮ ፡ አሁንም ፡ አንተ ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ያለኸው ፡
የአገሩ ፡ ገዥ ፡ ተንትናይ ፡ ደግሞ ፡ ሰተርቡዝ
ናይ ፡ በወንዝ ፡ ማዶም ፡ ያሉ ፡ ተባበሪዎቻችሁ ፡
፯ ፡ አፌርስከውያን ÷ ከዚያ ፡ ራቁ ፤ ይህም ፡ የእግ
ዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ተዉ ፤ የአ
ይሁድም ፡ አለቃና ፡ የአይሁድም ፡ ሽማግሌ
ዎች ፡ ይህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ በስፍ
፰ ፡ ራው ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ተዉአቸው ። ይህን ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ለአ
ይሁድ ፡ ሽማግሌዎች ፡ የምታደርጉትን ÷ በወ
ንዝ ፡ ማዶ ፡ ካለው ፡ አገር ፡ ከሚመጣው ፡ ግብር ፡
ከንጉሡ ፡ ገንዘብ ፡ ለእነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ወጪውን ፡
በትጋት ፡ እንድትሰጡአቸው ፡ ሥራም ፡ እንዳ
፱ ፡ ታስፈቱአቸው ፡ አዝዣለሁ ። ለሰማይ ፡ አም
ላክ ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የሚያስፈልገ
ውን ÷ ወይፈኖችና ፡ አውራ ፡ በጎች ፡ ጠቦቶ
ችም ÷ በኢየሩሳሌምም ፡ እንዳሉ ፡ እንደ ፡ ካህ
ናቱ ፡ ቃል ፡ ስንዴና ፡ ጨው ፡ የወይን ፡ ጠጅና ፡
ዘይት ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ያለማቋረጥ ፡ ስጡአቸው ።
፲ ፡ ይኸውም ፡ ለሰማይ ፡ አምላክ ፡ጣፋጭ ፡ ሽቱ ፡
የሆነውን ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡
ለንጉሡና ፡ ለልጆቹም ፡ ዕድሜ ፡ ይጸልዩ ፡
፲፩ ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ይህንም ፡ ትእዛዝ ፡ የሚለውጥ ፡
ሁሉ ÷ ምሰሶው ፡ ከቤቱ ፡ ተነቅሎ ፡ እርሱ ፡
ይሰቀልበት ፤ ቤቱም ፡ የጉድፍ ፡ መጣያ ፡
፲፪ ፡ ይደረግ ፡ ብዬ ፡ እዝዣለሁ ። ስሙንም ፡ በዚያ ፡
ያኖረው ፡ አምላክ ፡ ይህን ፡ ይለውጡ ፡ ዘንድ ፡
በኢየሩሳሌም ፡ ያለውንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ቤት ፡ ያፈርሱት ፡ ዘንድ ፡ እጃቸውን ፡ የሚዘረ
ጉትን ፡ ነገሥታትና ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ያጥፋ ።
እኔ ፡ ዳርዮስ ፡ ይህን ፡ አዝዣለሁ ፤ በትጋት ፡
ይፈጸም ።
፲፫ ፡ ንጉሡም ፡ ዳርዮስ ፡ እንደ ፡ ላከው ፡ ቃል ÷
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ያለ ፡ ገዥ ፡ ተን
ትናይ ፡ ደግሞ ፡ ሰተርቡዝናይ ፡ ተባበሪዎቻቸ
፲፬ ፡ ውም ፡ እንዲሁ ፡ ተግተው ፡ አደረጉ ። የአይ
ሁድም ፡ ሽማግሌዎች ፡ በነቢዩ ፡ በሐጌና ፡ በአዶ ፡
ልጅ ፡ በዘካርያስ ፡ ትንቢት ፡ ሠሩ ፡ ተከናወነላ
ቸውም ። እንደ ፡ እስራኤልም ፡ አምላክ ፡ ትእ
ዛዝ ÷ እንደ ፡ ፋርስም ፡ ነገሥታት ፡ እንደ ፡ ቂሮ
ስና ፡ እንደ ፡ ዳርዮስ ፡ እንደ ፡ አርጤክስስም ፡
፲፭ ፡ ትእዛዝ ፡ ሠርተው ፡ ፈጸሙ ። ይህም ፡ ቤት ፡
በንጉሡ ፡ በዳርዮስ ፡ መንግሥት ፡ በስድስተ
ኛው ፡ ዓመት ፡ አዳር ፡ በሚባል ፡ ወር ፡ በሦስተ
ኛው ፡ ቀን ፡ ተፈጸመ ።
፲፮ ፡ የእስራኤልም ፡ ልጆች ÷ ካህናትና ፡ ሌዋው
ያን ፡ የቀሩትም ፡ ምርኮኞች ÷ የዚህን ፡ የእግ
ዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ቅዳሴ ፡ በደስታ ፡ አደረጉ ።
፲፯ ፡ በዚህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ቅዳሴ ፡ መቶ ፡
ወይፈኖችና ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አውራ ፡ በጎች ፡
አራት ፡ መቶም ፡ ጠቦቶች ፡ አቀረቡ ፤ ስለ ፡
ኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡
ነገዶች ፡ ቍጥር ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ አሥራ ፡
ሁለት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፡ አቀረቡ ። በሙ ፲፰ ፡
ሴም ፡ መጽሐፍ ፡ እንደ ፡ ተጻፈው ፡ በኢየሩሳ
ሌም ፡ ባለው ፡ በእግዚአብሔር ፡ አገልግሎት ፡
ላይ ፡ ካህናቱን ፡ በየማዕርጋቸው ፡ ሌዋውያኑም ፡
በየክፍላቸው ፡ አቆሙ ።
ምርኮኞቹም ፡ በመጀመሪያው ፡ ወር ፡ በአ ፲፱ ፡
ሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ ፋሲካውን ፡ አደረጉ ።
ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑም ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡ ነጽ ፳ ፡
ተው ፡ ነበር ፤ ሁሉም ፡ ንጹሐን ፡ ነበሩ ፤ ለም
ርኮኞቹም ፡ ሁሉ ÷ ለወንድሞቻቸውም ፡ ለካህ
ናቱ ÷ ለራሳቸውም ፡ ፋሲካውን ፡ አረዱ ። ከም ፳፩ ፡
ርኮም ፡ ተመልሰው ፡ የመጡት ፡ የእስራኤል ፡
ልጆች ÷ የእስራኤልንም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ፡ ራሳቸውን ፡ ከም
ድር ፡ አሕዛብ ፡ ርኵሰት ፡ ለይተው ፡ ወደ ፡ እነ
ርሱ ፡ መጥተው ፡ የነበሩት ፡ ሁሉ ፡ በሉ ፤ እግ ፳፪ ፡
ዚአብሔር ፡ ደስ ፡ አሰኝቶአቸዋልና ÷ የእስራ
ኤልንም ፡ አምላክ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡
ለመሥራት ፡ እጃቸውን ፡ ያጸና ፡ ዘንድ ፡ የአሦ
ርን ፡ ንጉሥ ፡ ልብ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ መልሶአልና ፡
የቂጣውን ፡ በዓል ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በደስታ ፡ አደ
ረጉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

ከዚህም ፡ ነገር ፡ በኋላ ፡ በፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ በአ ፩ ፡
ርጤክስስ ፡ መንግሥት ፡ ዕዝራ ፡ የሠራያ ፡ ልጅ ÷
የዓዛርያስ ፡ ልጅ ÷ የኬልቅያስ ፡ ልጅ ÷ የሰሎም ፡ ፪ ፡
ልጅ ÷ የሳዶቅ ፡ ልጅ ÷ የአኪጦብ ፡ ልጅ ÷
የአማርያ ፡ ልጅ ÷ የዓዛርያስ ፡ ልጅ ÷ የመራዮት ፡ ፫ ፡
ልጅ ÷ የዘራእያ ፡ ልጅ ÷ የኦዚ ፡ ልጅ ÷ የቡቂ ፡ ፬ ፡
ልጅ ÷ የአቢሱ ፡ ልጅ ÷ የፊንሐስ ፡ ልጅ ÷ የአል ፭ ፡
ዓዛር ፡ ልጅ ÷ የታላቁ ፡ ካህን ፡ የአሮን ፡ ልጅ ÷
ይህ ፡ ዕዝራ ፡ ከባቢሎን ፡ ወጣ ፤ የእስራኤልም ፡ ፮ ፡
አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሰጠው ፡ በሙሴ ፡
ሕግ ፡ ፈጣን ፡ ጸሐፊ ፡ ነበረ ፤ የአምላኩም ፡ የእ
ግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ነበረችና ፡
ንጉሡ ፡ የሻውን ፡ ሁሉ ፡ ሰጠው ። ከእስራኤ ፯ ፡
ልም ፡ ልጆች ፡ ከካህናቱም ፡ ከሌዋውያኑም ፡
ከመዘምራኑም ፡ ከበረኞቹም ፡ ከናታኒምም ፡
በንጉሡ ፡ በአርጤክስስ ፡ በሰባተኛው ፡ ዓመት ፡
አያሌዎች ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወጡ ። በንጉ ፰ ፡
ሡም ፡ በሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ በአምስተኛው ፡
ወር ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ደረሰ ። በመጀመሪ ፱ ፡
ያውም ፡ ወር ፡ በአንደኛው ፡ ቀን ፡ ከባቢሎን ፡
ሊወጣ ፡ ጀመረ ÷ መልካሚቱም ፡ የአምላኩ ፡
እጅ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ነበረችና ፡ በአምስተኛ ፡
ወር ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
ደረሰ ። ዕዝራም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ፲ ፡
ይፈልግና ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ÷ ለእስራኤልም ፡
ሥርዓትንና ፡ ፍርድን ፡ ያስተምር ፡ ዘንድ ፡
ልቡን ፡ አዘጋጅቶ ፡ ነበር ።
ንጉሡም ፡ አርጤክስስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፲፩ ፡

ትእዛዝ፡ቃልና፡ለእስራኤል፡የሆነውን፡ሥር
ዓት፡ይጽፍ፡ለነበረው፡ለጸሐፊው፡ለካህኑ፡
ለዕዝራ፡የሰጠው፡የደብዳቤው፡ግልባጭ፡
፲፪ ይህ፡ነው፡— ከንጉሥ፡ነገሥት፡ከአርጤክስስ፡
ለሰማይ፡አምላክ፡ሕግ፡ጸሐፊ፡ለካህኑ፡ለዕ
፲፫ ዝራ÷ሙሉ፡ሰላም፡ይሁን፤በመንግሥቴ፡
ውስጥ፡ካሉ፡ከእስራኤል፡ሕዝብ፡ከካህናቱና፡
ከሌዋውያኑም፡ወደ፡ኢየሩሳሌም፡ይሄድ፡
ዘንድ፡የሚወድድ፡ሁሉ፡ከአንተ፡ጋር፡እን
፲፬ ዲሄድ፡አዝዣለሁ። በእጅህ፡እንዳለችው፡
እንደ፡አምላክህ፡ሕግ፡ይሁዳንና፡ኢየሩሳሌ
፲፭ ምን፡ትጐበኝ፡ዘንድ÷ንጉሡና፡አማካሪዎ
ቹም፡መኖሪያው፡በኢየሩሳሌም፡ለሆነው፡
ለእስራኤል፡አምላክ፡በፈቃዳቸው፡ያቀረቡ
፲፮ ትን፡ብርና፡ወርቅ÷በባቢሎንም፡አውራጃ፡
ሁሉ፡የምታገኘውን፡ብርና፡ወርቅ፡ሁሉ÷
ሕዝቡና፡ካህናቱም፡በኢየሩሳሌም፡ላለው፡
ለአምላካቸው፡ቤት፡በፈቃዳቸው፡የሚያቀር
ቡትን፡ትወስድ፡ዘንድ፡በንጉሡና፡በሰባቱ፡
፲፯ አማካሪዎች፡ተልከሃልና፡ስለዚህ፡በዚህ፡
ገንዘብ፡ወይፈኖችንና፡አውራ፡በጎችን፡ጠቦ
ቶችንም፡የእህላቸውንና፡የመጠጣቸውን፡
ቍርባን፡ተግተህ፡ግዛ፤በኢየሩሳሌምም፡
ባለው፡በአምላካችሁ፡ቤት፡መሠዊያ፡ላይ፡
፲፰ አቅርባቸው። ከቀረውም፡ብርና፡ወርቅ፡አን
ተና፡ወንድሞችህ፡ለማድረግ፡ደስ፡የሚያሰ
ኛችሁን፡ነገር፡እንደ፡አምላካችሁ፡ፈቃድ፡
፲፱ አድርጉ። ስለ፡አምላክህም፡ቤት፡አገልግ
ሎት፡የተሰጠህን፡ዕቃ፡በኢየሩሳሌም፡አም
፳ ላክ፡ፊት፡አሳልፈህ፡ስጥ። ከዚህም፡በላይ፡
ለማውጣት፡የሚያስፈልግህን፡ለአምላክህ፡
ቤት፡የሚያሻውን፡ነገር፡ከንጉሡ፡ቤተ፡መዛ
፳፩ ግብት፡አውጣ። እኔም፡ንጉሡ፡አርጤክስስ፡
በወንዝ፡ማዶ፡ላሉት፡በጅሮንዶች፡ሁሉ፡
ይህን፡ትእዛዝ፡ሰጥቻለሁ፡— የሰማይ፡አም
ላክ፡ሕግ፡ጸሐፊ፡ካህኑ፡ዕዝራ፡ከእናንተ፡
፳፪ የሚፈልገውን፡ሁሉ፡አዘጋጁለት፤እስከ፡
መቶ፡መክሊት፡ብርም፡ቢሆን÷እስከ፡
መቶም፡የቆሬስ፡መስፈሪያ፡ስንዴ÷እስከ፡
መቶም፡የበዶስ፡መስፈሪያ፡የወይን፡ጠጅ÷
እስከ፡መቶም፡የበዶስ፡መስፈሪያ፡ዘይት፡
ቢሆን÷ጨውም፡ያለ፡ልክ፡ቢሆን፡ስጡ።
፳፫ በንጉሡና፡በልጆቹ፡መንግሥት፡ላይ፡ቍጣ፡
እንዳይሆን÷የሰማይ፡አምላክ፡ያዘዘው፡ሁሉ፡
ለሰማይ፡አምላክ፡ቤት፡በሙሉ፡ይደረግ።
፳፬ ደግሞም፡በካህናቱና፡በሌዋውያን፡በመዘም
ራኑም፡በበረኞቹም፡በናታኒምም፡በዚህም፡
በእግዚአብሔር፡ቤት፡በሚሠሩ፡አገልጋዮች፡
ላይ፡ግብርና፡ቀረጥ፡መጥንም፡እንዳይጣል፡
፳፭ ብለን፡እናስታውቃችኋለን። አንተም፡ዕዝራ÷
በእጅህ፡እንዳለው፡እንደ፡አምላክህ፡ጥበብ፡
መጠን፡በወንዝ፡ማዶ፡ባሉ፡ሕዝብ፡ሁሉ፡
የአምላክህን፡ሕግ፡በሚያውቁ፡ሁሉ፡ላይ፡
ይፈርዱ፡ዘንድ፡ዳኞችንና፡ፈራጆች፡አስ
ነሣ፤የማያውቁትንም፡አስተምሩአቸው። ፳፮ የአ
ምላክህንም፡ሕግ÷የንጉሡንም፡ሕግ፡በማያ
ደርግ፡ሁሉ፡ላይ፡ሞት፡ወይም፡ስደት፡
ወይም፡ገንዘብን፡መወረስ፡ወይም፡ግዞት፡
በፍጥነት፡ይፈረድበት።

፳፯ ፳፰ በኢየሩሳሌም፡ያለውን፡የእግዚአብሔ
ርን፡ቤት፡ያሳምር፡ዘንድ፡እንደዚህ፡ያለውን፡
ነገር፡በንጉሡ፡ልብ፡ያኖረ÷በንጉሡም፡በአ
ማካሪዎቹም፡በንጉሡም፡ኃያላን፡አለቆች፡
ሁሉ፡ፊት፡ምሕረቱን፡ወደ፡እኔ፡የላከ፡የአ
ባቶቻችን፡አምላክ፡እግዚአብሔር፡ይባረክ።
እኔም፡በላዬ፡ባለችው፡በአምላኬ፡በእግዚ
አብሔር፡እጅ፡በረታሁ፤ከእኔም፡ጋር፡እን
ዲወጡ፡ከእስራኤል፡ዘንድ፡አለቆችን፡ሰበ
ሰብሁ።

## ምዕራፍ፡፰።

፩ በንጉሡ፡በአርጤክስስ፡መንግሥት፡ከእኔ፡
ጋር፡ከባቢሎን፡የወጡ፡የአባቶች፡ቤቶች፡
አለቆች፡እነዚህ፡ናቸው፡ትውልዳቸውም፡
፪ ይህ፡ነው፤ ከፊንሐስ፡ልጆች፡ጌርሶን÷ከኢ
ታምር፡ልጆች፡ዳንኤል÷ከዳዊት፡ልጆች፡
፫ ሐጡስ÷ከሴኬንያ፡ልጆች÷ከፋሮስ፡ልጆች፡
ዘካርያስ÷ከእርሱም፡ጋር፡መቶ፡አምሳ፡ወን
፬ ዶች፡በትውልድ፡ተቈጠሩ። ከፋሐት፡ሞዓብ፡
ልጆች፡የዘራእያ፡ልጅ፡ኤሊሆዔናይ÷ከእር
፭ ሱም፡ጋር፡ሁለት፡መቶ፡ወንዶች። ከሴኬንያ፡
ልጆች፡የየሕዚኤል፡ልጅ÷ከእርሱም፡ጋር፡
፮ ሦስት፡መቶ፡ወንዶች። ከዓዲን፡ልጆች፡
የዮናታን፡ልጅ፡ዔቤድ÷ከእርሱም፡ጋር፡
፯ አምሳ፡ወንዶች። ከኤላም፡ልጆች፡የጎቶ
ልያ፡ልጅ፡የሻያ÷ከእርሱም፡ጋር፡ሰባ፡
፰ ወንዶች። ከሰፋጥያስ፡ልጆች፡የሚካኤል፡
ልጅ፡ዝባድያ÷ከእርሱም፡ጋር፡ሰማንያ፡
፱ ወንዶች። ከኢዮአብ፡ልጆች፡የይሒኤል፡
ልጅ፡አብድዩ÷ከእርሱም፡ጋር፡ሁለት፡
፲ መቶ፡አሥራ፡ስምንት፡ወንዶች። ከሰሎሚት፡
ልጆች፡የዮሲፍያ፡ልጅ÷ከእርሱም፡ጋር፡
፲፩ መቶ፡ስድሳ፡ወንዶች። ከቤባይ፡ልጆች፡
የቤባይ፡ልጅ፡ዘካርያስ÷ከእርሱም፡ጋር፡
፲፪ ሀያ፡ስምንት፡ወንዶች። ከዓዝጋድ፡ልጆች፡
የሃቃጣን፡ልጅ፡ዮሐናን÷ከእርሱም፡ጋር፡
፲፫ መቶ፡አሥር፡ወንዶች። ከኋለኞቹ፡ከአዶኒ
ቃም፡ልጆች፡ስማቸው፡ይህ፡ነው፤ኤሊፋ
ላት÷ይዑኤል÷ሸማያ÷ከእነርሱም፡ጋር፡
፲፬ ስድሳ፡ወንዶች። ከበጉዋይ፡ልጆች፡ዑታ
ይና፡ዘቡድ÷ከእነርሱም፡ጋር፡ሰባ፡ወንዶች።

፲፭ ወደ፡አኅዋም፡ወደሚፈስስ፡ወንዝ፡ሰበሰ
ብኋቸው÷በዚያም፡ሦስት፡ቀን፡ሰፈርን፤
ሕዝቡንና፡ካህናቱን፡ስቈጥራቸው፡በዚያ፡
፲፮ ከሌዊ፡ልጆች፡ማንንም፡አላገኘሁም። ወደ፡
አለቆቹም፡ወደ፡አልዓዛር÷ወደ፡አርኤል÷
ወደ፡ሸማያ÷ወደ፡ኤልናታን÷ወደ፡ያሪብ÷
ወደ፡ኤልናታን÷ወደ፡ናታን÷ወደ፡ዘካር

ያስ ፥ ወደ ፡ ሚሱላም ፥ ደግሞም ፡ ወደ ፡ አዋቂዎቹ ፡ ወደ ፡ ዮያሪብና ፡ ወደ ፡ ኤልናታን ፡ ላክሁ ። ፲፯ በካሲፍያ ፡ ስፍራ ፡ ወደ ፡ ነበረው ፡ ወደ ፡ አለቃው ፡ ወደ ፡ አዶ ፡ ላክኋቸው ፤ ለአምላካችን ፡ ቤት ፡ አገልጋዮችን ፡ ያመጡልን ፡ ዘንድ ፡ በካሲፍያ ፡ ስፍራ ፡ ለሚኖሩት ፡ ለአዶና ፡ ለወንድሞቹ ፡ ለናታኒም ፡ የሚነግሩአቸውን ፡ በአፋቸው ፡ አደረግሁ ። ፲፰ በላያችንም ፡ መልካም ፡ በሆነው ፡ በአምላካችን ፡ እጅ ፡ ከእስራኤል ፡ ልጅ ፡ ከሌዊ ፡ ልጅ ፡ ከሞሖሊ ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ የነበረውን ፡ አስተዋይ ፡ ሰው ፡ ሰራብያን ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ አሥራ ፡ ስምንቱን ፡ ልጆቹንና ፡ ወንድሞቹን ፡ አመጡልን ። ፲፱ ደግሞም ፡ ሐሸብያን ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ከሜራሪ ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ የነበረውን ፡ የሻያናን ፡ ሀያውን ፡ ወንድሞቹንና ፡ ልጆቻቸውን ። ፳ ሌዋውያንንም ፡ እንዲያገለግሉ ፡ ዳዊትና ፡ አለቆቹ ፡ ከሰጡአቸው ፡ ናታኒም ፡ ውስጥ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ናታኒም ፡ አመጡ ፤ እነዚህም ፡ ሁሉ ፡ በስም ፡ በስማቸው ፡ ተጠሩ ።

፳፩ በአምላካችን ፡ ፊት ፡ ራሳችንን ፡ እናዋርድ ፡ ዘንድ ፥ ከእርሱም ፡ የቀናውን ፡ መንገድ ፡ ለእኛና ፡ ለልጆቻችን ፡ ለንብረታችንም ፡ ሁሉ ፡ እንለምን ፡ ዘንድ ፡ በዚያ ፡ በአኅዋ ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ ጾም ፡ አወጅሁ ። ፳፪ ንጉሡንም ፦ የአምላካችን ፡ እጅ ፡ በሚሹት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ለመልካም ፡ ነው ፤ ኃይሉና ፡ ቍጣው ፡ ግን ፡ እርሱን ፡ በሚተዉ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነው ፡ ብለን ፡ ተናግረን ፡ ነበርና ፡ በመንገድ ፡ ካለው ፡ ጠላት ፡ ያድኑን ፡ ዘንድ ፡ ጭፍራና ፡ ፈረሰኞች ፡ ከንጉሡ ፡ እለምን ፡ ዘንድ ፡ አፍሬ ፡ ነበርና ። ፳፫ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ጾምን ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ለመንን ፤ እርሱም ፡ ተለመነን ።

፳፬ ከካህናቱም ፡ አለቆች ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሰዎችን ፥ ሰራብያንና ፡ ሐሸቢያን ፡ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ አሥር ፡ ወንድሞቻቸውን ፡ ለየሁ ፤ ፳፭ ንጉሡና ፡ አማካሪዎቹ ፡ አለቆቹም ፡ በዚያም ፡ የተገኙት ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ያቀረቡትን ፡ ለአምላካችን ፡ ቤት ፡ የቀረበውን ፡ ብሩንና ፡ ወርቁን ፡ ዕቃውንም ፡ መዝኜ ፡ ሰጠኋቸው ። ፳፮ ስድስት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ መክሊት ፡ ብር ፥ አንድ ፡ መቶም ፡ መክሊት ፡ የብር ፡ ዕቃዎች ፥ አንድ ፡ መቶም ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፥ ፳፯ ሀያም ፡ በሺህ ፡ ዳሪክ ፡ የወርቅ ፡ ጽዋዎች ፥ ሁለትም ፡ እንደ ፡ ወርቅ ፡ የከበሩ ፡ ከጥሩ ፡ ከሚያንጸበርቅ ፡ ናስ ፡ የተሠሩ ፡ ዕቃዎች ፡ መዝኜ ፡ በእጃቸው ፡ ሰጠሁ ። ፳፰ እኔም ፦ እናንተ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተቀድሳችኋል ፥ ዕቃዎቹም ፡ ቅዱስ ፡ ናቸው ፤ ብሩና ፡ ወርቁም ፡ ለአባቶቻችን ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በፈቃድ ፡ የቀረበ ፡ ነው ፤ ፳፱ በካህናትና ፡ በሌዋውያን ፡ አለቆች ፡ በእስራኤልም ፡ አባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ፊት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ጓዳዎች ፡ ውስጥ ፡ እስክትመዝኑ ፡ ድረስ ፡ ተግታችሁ ፡ ጠብቁ ፡ አልኋቸው ። ፴ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ አምላካችን ፡ ቤት ፡ ይወስዱት ፡ ዘንድ ፡ ብሩንና ፡ ወርቁን ፡ ዕቃዎቹንም ፡ በሚዛን ፡ ተቀበሉ ።

፴፩ በመጀመሪያውም ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እንሄድ ፡ ዘንድ ፡ ከአኅዋ ፡ ወንዝ ፡ ተነሣን ፤ የአምላካችንም ፡ እጅ ፡ በላያችን ፡ ነበረ ፥ በመንገድም ፡ ከጠላትና ፡ ከሚሸምቅ ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ አዳነን ። ፴፪ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ደረስን ፥ በዚያም ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ተቀመጥን ። ፴፫ በአራተኛውም ፡ ቀን ፡ ብሩና ፡ ወርቁ ፡ ዕቃዎቹም ፡ በአምላካችን ፡ ቤት ፡ በካህኑ ፡ በኦርዮ ፡ ልጅ ፡ በሜሪሞት ፡ እጅ ፡ ተመዘኑ ፤ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የፊንሐስ ፡ ልጅ ፡ አልዓዛር ፡ ነበረ ፤ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ሌዋውያን ፡ የኢያሱ ፡ ልጅ ፡ ዮዛባትና ፡ የቢንዊ ፡ ልጅ ፡ ኖዓድያ ፡ ነበሩ ። ፴፬ ሁሉም ፡ በቍጥርና ፡ በሚዛን ፡ ተመዘነ ፤ ሚዛኑም ፡ ሁሉ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ተጻፈ ።

፴፭ ከምርኮም ፡ የወጡት ፡ ምርኮኞች ፡ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ወይፈኖች ፥ ዘጠና ፡ ስድስትም ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ ሰባ ፡ ሰባትም ፡ ጠቦቶች ፥ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፡ አቀረቡ ። ይህ ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ነበረ ። ፴፮ የንጉሡንም ፡ ትእዛዝ ፡ በወንዙ ፡ ማዶ ፡ ላሉት ፡ ለንጉሡ ፡ ሹማምቶችና ፡ ገዦች ፡ ሰጡ ፤ እነርሱም ፡ ሕዝቡንና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ አገዙ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ይህም ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ አለቆቹ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ቀርበው ፦ የእስራኤል ፡ ሕዝብ ፡ ካህናቱም ፡ ሌዋውያኑም ፡ እንደ ፡ ከነዓናውያን ፡ እንደ ፡ ኬጢያውያን ፡ እንደ ፡ ፌርዛውያን ፡ እንደ ፡ ኢያቡሳውያን ፡ እንደ ፡ አሞናውያን ፡ እንደ ፡ ሞዓባውያን ፡ እንደ ፡ ግብጻውያንና ፡ እንደ ፡ አሞራውያን ፡ ርኵሰት ፡ ያደርጋሉ ፡ እንጂ ፡ ከምድር ፡ አሕዛብ ፡ አልተለዩም ፤ ፪ ለራሳቸውና ፡ ለልጆቻቸውም ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ ወስደዋል ፥ የተቀደሰውንም ፡ ዘር ፡ ከምድር ፡ አሕዛብ ፡ ጋር ፡ ደባልቀዋል ፤ አስቀድሞም ፡ አለቆቹና ፡ ሹማምቶቹ ፡ በዚህ ፡ መተላለፍ ፡ መጀመሪያ ፡ ሆነዋል ፡ አሉኝ ። ፫ ይህንም ፡ ነገር ፡ በሰማሁ ፡ ጊዜ ፡ ልብሴንና ፡ መጐናጸፊያዬን ፡ ቀደድሁ ፥ የራሴንና ፡ የጢሜንም ፡ ጠጕር ፡ ነጨሁ ፥ ደንግጬም ፡ ተቀመጥሁ ። ፬ ስለ ፡ ምርኮኞቹም ፡ መተላለፍ ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ ቃል ፡ የሚፈሩ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ተሰበሰቡ ፤ እኔም ፡ እስከ ፡ ሠርክ ፡ መሥዋዕት ፡ ድረስ ፡ ደንግጬ ፡ ተቀመጥሁ ።

፭ በሠርክም ፡ መሥዋዕት ፡ ጊዜ ፡ ልብሴና ፡ መጐናጸፊያዬ ፡ እንደ ፡ ተቀደደ ፡ ሆኖ ፡ ከመዋረዴ ፡ ተነሣሁ ፤ በጕልበቴም ፡ ተንበርክኬ ፡ ወደ ፡ አም

ላኬ፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ እጄን፡ ዘረጋሁ።
፮፤ እንዲህም፡ አልሁ፡— አምላኬ፡ ሆይ ÷ ኃጢአ
ታችን፡ በራሳችን፡ ላይ፡ በዝቶአልና ÷ በደላች
ንም፡ ወደ፡ ሰማይ፡ ከፍ፡ ከፍ፡ ብሎአልና፡ አም
ላኬ፡ ሆይ ÷ ፊቴን፡ ወደ፡ አንተ፡ አነሣ፡ ዘንድ፡
፯፤ አፍራለሁ ÷ እፈራማለሁ ። ከአባቶቻችን ፡
ዘመን፡ ጀምረን፡ እስከ፡ ዛሬ፡ ድረስ፡ እጅግ፡
በድለናል ፤ ዛሬም፡ እንደ፡ ሆነው፡ ስለ፡ ኃጢአ
ታችን፡ እኛና፡ ንጉሦቻችን፡ ካህናቶቻችንም፡
ለሰይፍና ፡ ለምርኮ ፡ ለብዝበዛና ፡ ለእፍረት ፡
፰፤ በምድር ፡ ነገሥታት ፡ እጅ ፡ ተጣልን ። አሁ
ንም ፡ ቅሬታ ፡ ይተውልን ፡ ዘንድ ÷ በተቀደሰ
ውም ፡ ስፍራው ፡ ችንካርን ፡ ይሰጠን ፡ ዘንድ ÷
አምላካችንም ፡ ዓይናችንን ፡ ያበራ ፡ ዘንድ ÷
በባርነትም ፡ ሳለን ፡ ጥቂት ፡ የሕይወት ፡ መታ
ደስን፡ ይሰጠን፡ ዘንድ፡ ለጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ከአም
ላካችን፡ ከእግዚአብሔር፡ ሞገስ፡ ተሰጥቶናል።
፱፤ ባሪያዎች፡ ነንና ÷ አምላካችን፡ ግን፡ በባርነታ
ችን ፡ አልተወንም ፤ የሕይወት ፡ መታደስን ፡
ይሰጠን፡ ዘንድ ÷ የአምላካችንንም፡ ቤት፡ እን
ሥራ ፡ ዘንድ ÷ የተፈታውንም ፡ እንጠግን ፡
ዘንድ ÷ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ ቅጥር ፡
ይደረግልን፡ ዘንድ፡ በፋርስ፡ ነገሥታት፡ ፊት፡
፲፤፲፩፤፲፪፤ ምሕረቱን ፡ ሰጠን ። አሁንስ ፡ አምላካችን ፡
ሆይ ፡— ትወርሱአት ፡ ዘንድ ፡ የምትገቡባት ፡
ምድር ፡ በምድር ፡ አሕዛብ ፡ ርኵሰት ፡ ረከሳ
ለች ÷ ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳርም ፡ ድረስ ፡ ከርኵሰታ
ቸው ፡ ከጸያፍ ፡ ሥራቸውም ፡ ተሞልታለች ፤
አሁንም፡ ትበረቱ፡ ዘንድ ÷ የምድሩንም፡ ፍሬ፡
ትበሉ ፡ ዘንድ ÷ ለዘላለምም ፡ ለልጆቻችሁ ፡
ታወርሱአት ፡ ዘንድ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችሁን ፡
ለልጆቻቸው ፡ አትስጡ ÷ ሴቶች ፡ ልጆቻቸው
ንም ፡ ለልጆቻችሁ ፡ አትውሰዱ ÷ ሰላማቸው
ንና ፡ ደኅንነታቸውንም ፡ ለዘላለም ፡ አትሹ ፡
ብለህ ፡ በባሪያዎችህ ፡ በነቢያት ፡ ያዘዝኸውን ፡
ትእዛዝ ፡ ትተናልና ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ምን ፡ እንላ
፲፫፤ ለን ? ስለ ፡ ክፉ ፡ ሥራችንና ፡ ስለ ፡ ታላቁ ፡ በደላ
ችን ፡ ከገኘን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በኋላ ÷ አንተ ፡ አም
ላካችን ፡ እንደ ፡ ኃጢአታችን ፡ ብዛት ፡ አልቀ
ሠፍኸንም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ቅሬታን ፡ ሰጠኸን ።
፲፬፤ በውኑ ፡ ተመልሰን ፡ ትእዛዝህን ፡ እናፈርስ ፡
ዘንድ ÷ ርኩስ ፡ ሥራን ፡ ከሚሠሩ ፡ ከእነዚህም ፡
አሕዛብ ፡ ጋር ፡ እንገባ ፡ ዘንድ ፡ ይገባናልን? አን
ተስ፡ ቅሬታ፡ የሌለንና፡ የማናመልጥ፡ እስክንሆን፡
፲፭፤ ድረስ ፡ እንድታጠፋን ፡ አትቈጣንም ? አቤቱ ፡
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ አንተ ፡ ጻድቅ ፡
ነህ ፤ ዛሬም ፡ እንደ ፡ ሆነው ፡ እኛ ፡ አምልጠን ፡
ቀርተናል ፤ እነሆ ፡ በፊትህ ፡ በበደላችን ፡ አለን ፤
ስለዚህ ፡ በፊትህ ፡ ሊቆም ፡ የሚችል ፡ የለም ።

ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፤ ዕዝራም ፡ እያለቀሰና ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
ፊት ፡ እየወደቀ ፡ በጸለየና ፡ በተናዘዘ ፡ ጊዜ ፡ ከእ
ስራኤል ፡ ዘንድ ፡ የወንድና ፡ የሴት ፡ የሕፃና
ትም ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ጉባኤ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡
፪፤ ተሰበሰበ ፤ ሕዝቡም ፡ እጅግ ፡ አለቀሱ ። ከኤ
ላም ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ የነበረም ፡ የይሒኤል ፡
ልጅ ፡ ሴኬንያ ፡ ዕዝራን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገ
ረው ፡— አምላካችንን ፡ በድለናል ፤ የምድርን ፡
አሕዛብ ፡ እንግዶች ፡ ሴቶችን ፡ አግብተናል ፤
አሁን ፡ ግን ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ገና ፡ ለእስራኤል ፡
፫፤ ተስፋ ፡ አለ ። አሁንም ፡ እንደ ፡ ጌታዬና ፡ የአ
ምላካችንን ፡ ትእዛዝ ፡ እንደሚፈሩት ፡ ምክር ÷
ሴቶችን ፡ ሁሉ ፡ ከእነርሱም ፡ የተወለዱትን ፡
እንሰድድ ፡ ዘንድ ፡ ከአምላካችን ፡ ጋር ፡ ቃል ፡
ኪዳን ፡ እናድርግ ፤ እንደ ፡ ሕጉም ፡ ይደረግ ።
፬፤ ይህም ፡ ነገር ፡ ለአንተ ፡ ይገባልና ÷ እኛም ፡ ከአ
ንተ ፡ ጋር ፡ ነንና ፡ ተነሣ ÷ አይዞህ ፡ አድርገው ።
፭፤ ዕዝራም ፡ ተነሣ ፤ አለቆቹንና ፡ ካህናቱን ፡ ሌዋ
ውያኑንም ፡ እስራኤልንም ፡ ሁሉ ፡ እንደዚህ ፡
ቃል ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አማለ ፤ እነርሱም ፡
፮፤ ማሉ ። ዕዝራም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ፊት ፡
ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ኤልያሴብ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ዮሐ
ናን ፡ ጓዳ ፡ ገባ ፤ ስለ ፡ ምርኮኞቹም ፡ ኃጢአት ፡
ያለቅስ ፡ ነበርና ፡ ገብቶ ፡ እንጀራ ፡ አልበላም ÷
፯፤፰፤ ውኃም ፡ አልጠጣም ። ምርኮኞቹም ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እንዲሰበሰቡ ÷ እንደ ፡ አለ
ቆቹና ፡ እንደ ፡ ሽማግሌዎችም ፡ ምክር ፡ በሦ
ስት ፡ ቀን ፡ ውስጥ ፡ ያልመጣ ፡ ሁሉ ፡ ንብረቱ ፡
ሁሉ ፡ እንዲወረስ ÷ እርሱም ፡ ከምርኮው ፡
ጉባኤ ፡ እንዲለይ ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡
ላይ ፡ አዋጅ ፡ ነገሩ ።
፱፤ ሦስት ፡ ቀንም ፡ ሳያልፍ ፡ በዘጠኝኛው ፡ ወር ፡
ከወሩም ፡ በሀያኛው ፡ ቀን ፡ የይሁዳና ፡ የብንያም ፡
ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተሰበሰቡ ። ሕዝ
ቡም ፡ ሁሉ ፡ ስለዚህ ፡ ነገርና ፡ ስለ ፡ ታላቁ ፡ ዝናብ ፡
እየተንቀጠቀጡ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ፊት ፡
፲፤ ባለው ፡ አደባባይ ፡ ተቀመጡ ። ካህኑም ፡ ዕዝራ ፡
ተነሥቶ ፡— ተላልፋችኋል ፤ የእስራኤልን ፡
በደል ፡ ታበዙ ፡ ዘንድ ፡ እንግዶችን ፡ ሴቶች ፡
፲፩፤ አግብታችኋል ። አሁንም ፡ ለአባቶቻችሁ ፡ አም
ላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተናዘዙ ÷ ደስ ፡ የሚያ
ሰኘውንም ፡ አድርጉ ፤ ከምድርም ፡ አሕዛብና ፡
፲፪፤ ከእንግዶች ፡ ሴቶች ፡ ተለዩ ፡ አላቸው ። ጉባኤ
ውም ፡ ሁሉ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ መልሰው ፡ እን
ዲህ ፡ አሉ ፡— እንደ ፡ ተናገርኸን ፡ እናደርግ ፡
፲፫፤ ዘንድ ፡ ይገባናል ። ነገር ፡ ግን ፡ የሕዝቡ ፡ ቍጥር ፡
ብዙ ፡ ነው ÷ ጊዜውም ፡ የትልቅ ፡ ዝናብ ፡ ጊዜ ፡
ነው ÷ በሜዳም ፡ ልንቆም ፡ አንችልም ፤ በዚ
ህም ፡ ነገር ፡ እጅግ ፡ በድለናልና ፡ ይህ ፡ ሥራ ፡
የአንድ ፡ ወይም ፡ የሁለት ፡ ቀን ፡ ሥራ ፡ አይደ
፲፬፤ ለም ። አለቆቻችንም ፡ በጉባኤው ፡ ሁሉ ፡
ፋንታ ፡ ይቁሙ ፤ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ የአምላካ
ችን ፡ጽኑ ፡ ቍጣ ፡ ከእኛ ፡ ይመለስ ፡ ዘንድ ፡
እንግዶቹን ፡ ሴቶች ፡ ያገቡት ፡ በከተሞቻችን ፡
ያሉት ፡ ሁሉ ፡ በተቀጠረው ፡ ጊዜ ፡ ይምጡ ÷
ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ የከተማ ፡ ሁሉ ፡ ሽማግሌዎ
፲፭፤ ችና ፡ ፈራጆች ፡ ይምጡ ። ነገር ፡ ግን ፡ የአሣ

ሄል ፡ ልጅ ፡ ዮናታንና ፡ የቴቁዋ ፡ ልጅ ፡ የሕዝያ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ተቃወሙ ፤ ሚሱላምና ፡ ሌዋዊውም ፡ ሳበታይ ፡ ረዱአቸው ።

፲፮ ምርኮኞቹም ፡ እንዲህ ፡ አደረጉ ፤ ካህኑ ፡ ዕዝራም ፡ የአባቶችም ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ በየአባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ ተለዩ ፥ ሁሉም ፡ በየስማቸው ፡ ተጻፉ ፤ በአሥረኛውም ፡ ወር ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ነገሩን ፡ ይመረምሩ ፡ ዘንድ ፡ ፲፯ ተቀመጡ ። እስከ ፡ መጀመሪያውም ፡ ወር ፡ እስከ ፡ መጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ሠርተው ፡ እንግዶቹን ፡ ሴቶች ፡ ያገቡትን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ መርምረው ፡ ጨረሱ ።

፲፰ ከካህናቱም ፡ ወገን ፡ ልጆች ፡ እንግዶቹን ፡ ሴቶች ፡ ያገቡ ፡ ሰዎች ፡ ተገኙ ፤ ከኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ ከኢያሱ ፡ ልጆችና ፡ ከወንድሞቹ ፥ መዕ ፲፱ ሤያ ፥ አልዓዛር ፥ ያሪብ ፥ ጎዶልያስ ። ሚስቶቻቸውን ፡ ይፈቱ ፡ ዘንድ ፡ እጃቸውን ፡ ሰጡ ፤ ስለ ፡ በደላቸውም ፡ ከመንጋው ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ ፳ በግ ፡ ስለበደል ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረቡ ። ከኢ ፳፩ ሜር ፡ ልጆችም ፤ አናኒና ፡ ዝባድያ ። ከካሪም ፡ ልጆችም ፤ መዕሤያ ፥ ኤልያስ ፥ ሸማያ ፥ ይሒ ፳፪ ኤል ፥ ዖዝያ ። ከፋስኩር ፡ ልጆችም ፤ ኤልዮዔናይ ፥ መዕሤያ ፥ ይስማኤል ፥ ናትናኤል ፥ ዮዛባት ፥ ኤልዓሣ ።

፳፫ ከሌዋውያንም ፤ ዮዛባት ፥ ሰሜኢ ፥ ቆሊጣስ ፡ የሚባል ፡ ቆልያ ፥ ፈታያ ፥ ይሁዳ ፥ አልዓዛር ።

፳፬ ከመዘምራንም ፤ ኤልያሴብ ፤ ከበረኞችም ፤ ሰሎም ፥ ጤሌም ፥ ኡሪ ።

፳፭ ከእስራኤልም ፤ ከፋሮስ ፡ ልጆች ፤ ራምያ ፥ ይዝያ ፥ መልክያ ፥ ሚያሚን ፥ አልዓዛር ፥ መልክያ ፥ በናያስ ። ፳፮ ከኤላም ፡ ልጆችም ፤ መታንያ ፥ ዘካርያስ ፥ ይሒኤል ፥ አብዲ ፥ ይሬሞት ፥ ኤልያ ። ፳፯ ከዛቱዕ ፡ ልጆችም ፤ ዔሊዮዔናይ ፥ ኢልያሴብ ፥ መታንያ ፥ ይሬሞት ፥ ዛባድ ፥ ዓዚዛ ። ፳፰ ከቤባይ ፡ ልጆችም ፤ ይሆሐናን ፥ ሐናንያ ፥ ዘባይ ፥ አጥላይ ። ፳፱ ከባኒ ፡ ልጆችም ፤ ሚሱላም ፥ መሉክ ፥ ዓዳያ ፥ ያሱብ ፥ ሸዓል ፥ ራሞት ። ፴ ከፈሐት ፡ ሞዓብ ፡ ልጆችም ፤ ዓድና ፥ ክላል ፥ በናያስ ፥ መዕሤያ ፥ መታንያ ፥ ባስልኤል ፥ ቢንዊ ፥ ምናሴ ። ፴፩ ከካሪም ፡ ልጆችም ፤ አልዓዛር ፥ ይሺያ ፥ መልክያ ፥ ሸማያ ፥ ስምዖን ፥ ፴፪ ብንያም ፥ መሉክ ፥ ሰማራያ ። ፴፫ ከሐሱም ፡ ልጆችም ፤ መትናይ ፥ መተታ ፥ ዛባድ ፥ ኤሊፋላት ፥ ይሬማይ ፥ ምናሴ ፥ ሰሜኢ ። ፴፬ ከባኒ ፡ ልጆችም ፤ መዕዳይ ፥ ዓምራም ፥ ኡኤል ፥ ፴፭ በናያስ ፥ ቤድያ ፥ ኬልቅያ ፥ ፴፮ ወንያ ፥ ሜሬሞት ፥ ኤልያሴብ ፥ ፴፯ መታንያ ፥ መትናይ ፥ የዕሡ ፥ ፴፰ ባኒ ፥ ቢንዊ ፥ ሰሜኢ ፥ ፴፱ ሰሌምያ ፥ ናታን ፥ ዓዳያ ፥ ፵ መክነድባይ ፥ ሴሴይ ፥ ሸራይ ፥ ፵፩ ኤዝርኤል ፥ ሰሌምያ ፥ ሰማራያ ፥ ፵፪ ሰሎም ፥ አማርያ ፥ ዮሴፍ ። ፵፫ ከናባው ፡ ልጆችም ፤ ይዒኤል ፥ መቲትያ ፥ ዛባድ ፥ ዘቢና ፥ ያዳይ ፥ ኢዮኤል ፥ በናያስ ። ፵፬ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ እንግዶቹን ፡ ሚስቶች ፡ አግብተው ፡ ነበር ፤ ከእነዚህም ፡ ሚስቶች ፡ አያሌዎቹ ፡ ልጆችን ፡ ወልደው ፡ ነበር ።

# መጽሐፈ ፡ ነህምያ ።

(እርሱም ፡ በግዕዝ ፡ የመጽሐፈ ፡ ዕዝራ ፡ ክፍል ፡ ነው ።)

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ የሐካልያ ፡ ልጅ ፡ የነህምያ ፡ ቃል ።

በሀያኛው ፡ ዓመት ፡ በካሴሉ ፡ ወር ፡ እንዲህ ፡ ፪ ሆነ ፤ እኔ ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡ሳለሁ ፥ ከወንድሞቼ ፡ አንዱ ፡ አናኒ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ሌሎች ፡ ሰዎች ፡ ከይሁዳ ፡ መጡ ፤ እኔም ፡ የዳኑትን ፡ ከምርኮ ፡ የተረፉትን ፡ የአይሁድን ፡ ነገር ፡ የኢየሩሳሌም ፫ ንም ፡ ነገር ፡ ጠየቅኋቸው ። እነርሱም ፦ በዚያ ፡ ስፍራ ፡ ያሉት ፡ ከምርኮ ፡ የተረፉት ፡ ቅሬታዎች ፡ በታላቅ ፡ መከራና ፡ ስድብ ፡ አሉ ፤ የኢየሩሳሌምም ፡ ቅጥር ፡ ፈርሶአል ፥ በሮችዋም ፡ በእሳት ፡ ተቃጥለዋል ፡ አሉኝ ።

፬ ይህንም ፡ ቃል ፡ በሰማሁ ፡ ጊዜ ፡ ተቀምጬ ፡ አለቀስሁ ፥ አያሌ ፡ ቀንም ፡ አዝን ፡ ነበር ፤ በሰማይም ፡ አምላክ ፡ ፊት ፡ እጾምና ፡ እጸልይ ፡ ነበር ፥ ፭ እንዲህም ፡ አልሁ ፦ አቤቱ ፡ የሰማይ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ ለሚወድዱህና ፡ ትእዛዝህን ፡ ለሚያደርጉ ፡ ቃል ፡ ኪዳንንና ፡ ምሕረትን ፡ የምትጠ ፮ ብቅ ፥ ታላቅና ፡ የተፈራህ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ዛሬ ፡ በፊትህ ፡ ስለ ፡ ባሪያዎችህ ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሌሊትና ፡ ቀን ፡ የምጸልየውን ፡ጸሎት ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡ ጆሮህ ፡ ያድምጥ ፥ ዓይኖችህም ፡ ይከፈቱ ፤ በአንተ ፡ ላይም ፡ ያደረግነውን ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ኃጢአት ፡ እናዘዝልሃለሁ ፤ እኔና ፡ የአባቴም ፡ ቤት ፡ በድ ፯ ለናል ። እኛም ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡ ክፉ ፡ ሠርተናል ፤ ለባሪያህም ፡ ለሙሴ ፡ ያዘዝኸውን ፡ ትእዛዝና ፡ ሥርዓት ፡ ሕግም ፡ አልጠበቅንም ። ፰ ፱ አሁንም ፦ ብትተላለፉ ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ እበትናችኋለሁ ፤ ወደ ፡ እኔ ፡ ብትመለሱ ፡ ግን ፥ ትእዛዜንም ፡ ብትጠብቁ ፡ ብታደርጓትም ፥ ከእናንተ ፡ ሰዎች ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ምንም ፡ ቢበተኑ ፡ ከዚያ ፡ እሰበስባቸዋለሁ ፥ ስሜም ፡ ይኖርበት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መረጥሁት ፡ ስፍራ ፡ አመጣቸዋለሁ ፡ ብለህ ፡ ለባሪያህ ፡ ለሙሴ ፡ ያዘዝኸውን ፡ ቃል ፡ አባክህ ፡ አስብ ። ፲ እነዚህም ፡ በታላቅ ፡ ኃይልህና ፡ በብርቱ ፡ እጅህ ፡ የተቤዠሃቸው ፡ ባሪያዎችህና ፡ ሕዝብህ ፡ ናቸው ። ፲፩ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ጆሮህ ፡ የባሪያህን ፡

ጸሎት ፥ ስምህንም ፡ ይፈሩ ፡ ዘንድ ፡ የሚወድዱ
ትን ፡ የባሪያዎችህን ፡ ጸሎት ፡ ያድምጥ ፤ ዛሬም ፡
ለባሪያህ ፡ አከናውንለት ፥ በዚህም ፡ ሰው ፡ ፊት ፡
ምሕረትን ፡ ስጠው ። እኔም ፡ ለንጉሡ ፡ ጠጅ ፡
አሳላፊው ፡ ነበርሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፤ በንጉሡ ፡ በአርጤክስስ ፡ በሀያኛው ፡ ዓመት ፡
በኒሳን ፡ ወር ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ በፊቱ ፡ በነበረ ፡
ጊዜ ፡ ጠጁን ፡ አንሥቼ ፡ ለንጉሡ ፡ ሰጠሁት ።
ቀድሞ ፡ ግን ፡ በፊቱ ፡ ያለ ፡ ኀዘን ፡ አኖር ፡ ነበር ።
፪፤ ንጉሡም ፦ ሳትታመም ፡ ፊትህ ፡ ለምን ፡
አዘነ ? ይህ ፡ የልብ ፡ ኀዘን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
ሌላ ፡ ነገር ፡ አይደለም ፡ አለኝ ። እጅግም ፡ ብዙ ፡
፫፤ አድርጌ ፡ ፈራሁ ። ንጉሡንም ፦ ንጉሡ ፡
ሺህ ፡ ዓመት ፡ ይንገሥ ፤ የአባቶቼ ፡ መቃብር ፡
ያለባት ፡ ከተማ ፡ ተፈትታለችና ፥ በሮችዋም ፡
በእሳት ፡ ተቃጥለዋልና ፡ ፊቴ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አይ
፬፤ ዘን ? አልሁት ። ንጉሡም ፦ ምን ፡ ትለምነኛ
ለህ ? አለኝ ። እኔም ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አምላክ ፡
፭፤ ጸለይሁ ። ንጉሡንም ፦ ንጉሡን ፡ ደስ ፡ ቢያ
ሰኝህ ፥ ባሪያህም ፡ በፊትህ ፡ ሞገስ ፡ ቢያገኝ ፥
እሠራው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ወደ ፡ አባቶቼ ፡
፮፤ መቃብር ፡ ከተማ ፡ ስደደኝ ፡ አልሁት ። ንግሥ
ቲቱም ፡ በአጠገቡ ፡ ተቀምጣ ፡ ሳለች ፡ ንጉሡ ፦
መንገድህ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ይሆናል ?
መቼስ ፡ ትመለሳለህ ? አለኝ ። ንጉሡም ፡ ይሰ
ድደኝ ፡ ዘንድ ፡ ደስ ፡ አለው ፤ እኔም ፡ ዘመ
፯፤ ኑን ፡ ቀጠርሁለት ። ንጉሡንም ፦ ንጉሡ ፡
ደስ ፡ ቢለው ፥ እስከ ፡ ይሁዳ ፡ አገር ፡ እንዲያ
ደርሱኝ ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ላሉት ፡ ገዦች ፡ ደብ
፰፤ ዳቤ ፡ ይሰጠኝ ፤ በቤቱም ፡ አጠገብ ፡ ላለው ፡
ለግንብ ፡ በሮች ፥ ለከተማውም ፡ ቅጥር ፥ ለምገ
ባበትም ፡ ቤት ፡ እንጨት ፡ እንዲሰጠኝ ፡ ለን
ጉሡ ፡ ዱር ፡ ጠባቂ ፡ ለአሳፍ ፡ ደብዳቤ ፡ ይሰ
ጠኝ ፡ አልሁት ። ንጉሡም ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ መል
ካም ፡ እንደ ፡ ሆነችው ፡ እንደ ፡ አምላኬ ፡ እጅ ፡
ሰጠኝ ።

፱፤ በወንዙም ፡ ማዶ ፡ ወዳሉት ፡ አለቆች ፡
መጥቼ ፡ የንጉሡን ፡ ደብዳቤ ፡ ሰጠኋቸው ።
ንጉሡም ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ የሠራዊቱን ፡ አለቆችና ፡
፲፤ ፈረሰኞች ፡ ሰደደ ። ሖሮናዊውም ፡ ሰንባላጥና ፡
ባሪያው ፡ አሞናዊ ፡ ጦብያ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡
መልካምን ፡ ነገር ፡ የሚሻ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ መጣ ፡
፲፩፤ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ተበሳጩ ። ወደ ፡ ኢየ
ሩሳሌምም ፡ ደረስሁ ፥ በዚያም ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡
፲፪፤ ያህል ፡ ተቀመጥሁ ። በሌሊትም ፡ ተነሣሁ ፥
ከእኔም ፡ ጋር ፡ አያሌ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ እግዚአ
ብሔርም ፡ ለኢየሩሳሌም ፡ አደርገው ፡ ዘንድ ፡
በልቤ ፡ ያኖረውን ፡ ለማንም ፡ አላስታወቅሁም ፤
ተቀምጬበት ፡ ከነበረው ፡ እንስሳ ፡ በቀር ፡
ከእኔ ፡ ጋር ፡ ምንም ፡ እንስሳ ፡ አልነበረም ።
፲፫፤ በሸለቆውም ፡ በር ፡ ወጣሁ ፥ ወደ ፡ ዘንዶውም ፡
ምንጭና ፡ ወደ ፡ ጕድፍ ፡ መጣያው ፡ በር ፡
ሄድሁ ፤ የፈረሰውንም ፡ የኢየሩሳሌምን ፡ ቅጥር ፥
በእሳትም ፡ የተቃጠሉትን ፡ በሮችዋን ፡ ተመ
፲፬፤ ለከትሁ ። ወደ ፡ ምንጩም ፡ በርና ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ መዋኛ ፡ አለፍሁ ፤ ተቀምጬበትም ፡
የነበረው ፡ እንስሳ ፡ የሚያልፍበት ፡ ስፍራ ፡
፲፭፤ አልነበረም ። በሌሊትም ፡ በፈፋው ፡ በኩል ፡
ወጥቼ ፡ ቅጥሩን ፡ ተመለከትሁ ፤ ዘወርም ፡ ብዬ ፡
በሸለቆው ፡ በር ፡ ገባሁ ፥ እንዲሁም ፡ ተመለ
፲፮፤ ስሁ ። ሹማምቱ ፡ ግን ፡ ወዴት ፡ እንደ ፡ ሄድሁ ፥
ምን ፡ እንዳደረግሁም ፡ አላወቁም ፡ ነበር ፤ ለአ
ይሁድና ፡ ለካህናቱ ፥ ለታላላቆችና ፡ ለሹማም
ቱም ፥ ሥራም ፡ ይሠሩ ፡ ለነበሩት ፡ ለሌሎች ፡
ገና ፡ አልተናገርሁም ፡ ነበር ።

፲፯፤ እኔም ፦ እኛ ፡ ያለንበትን ፡ ጕስቍልና ፥
ኢየሩሳሌም ፡ እንደ ፡ ፈረሰች ፥ በሮችዋም ፡
በእሳት ፡ እንደ ፡ ተቃጠሉ ፡ ታያላችሁ ፤ አሁ
ንም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ መሳለቂያ ፡ እንዳን
ሆን ፡ ኑና ፡ የኢየሩሳሌምን ፡ ቅጥር ፡ እንሥራ ፡
፲፰፤ አልኋቸው ። የአምላኬም ፡ እጅ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡
መልካም ፡ እንደ ፡ ሆነች ፥ ንጉሡም ፡ የነገረኝን ፡
ቃል ፡ ነገርኋቸው ። እነርሱም ፦ እንነሣና ፡
እንሥራ ፡ አሉ ። እጃቸውንም ፡ ለበጎ ፡ ሥራ ፡
፲፱፤ አበረቱ ። ሖሮናዊውም ፡ ሰንባላጥ ፥ ባሪያውም ፡
አሞናዊው ፡ ጦቢያ ፥ ዓረባዊውም ፡ ጌሳም ፡
በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ በንቀት ፡ ሳቁብን ፥ ቀላል ፡ አድ
ርገውንም ፦ ይህ ፡ የምታደርጉት ፡ ነገር ፡ ምን
ድር ፡ ነው ? በውኑ ፡ በንጉሡ ፡ ላይ ፡ ትሸፍቱ ፡
፳፤ ዘንድ ፡ ትወድዳላችሁን ? አሉ ። እኔም ፡
መልሼ ፦ የሰማይ ፡ አምላክ ፡ ያከናውንልናል ፥
እኛም ፡ ባሪያዎቹ ፡ ተነሥተን ፡ እንሠራለን ፤
እናንተ ፡ ግን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ እድል ፡ ፈን
ታና ፡ መብት ፡ መታሰቢያም ፡ የላችሁም ፡ አል
ኋቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፤ ታላቁም ፡ ካህን ፡ ኤልያሴብ ፡ ወንድሞቹም ፡
ካህናት ፡ ተነሥተው ፡ የበግ ፡ በር ፡ ሠሩ ፤ ቀደ
ሱትም ፥ ሳንቃዎቹንም ፡ አቆሙ ፤ እስከ ፡ ሃሜአ ፡
ግንብና ፡ እስከ ፡ ሐናንኤል ፡ ግንብ ፡ ድረስ ፡ ቀደ
፪፤ ሱት ። በአጠገቡ ፡ የኢያሪኮ ፡ ሰዎች ፡ ሠሩ ፤
በአጠገባቸውም ፡ የአምሪ ፡ ልጅ ፡ ዘኩር ፡ ሠራ ።
፫፤ የሃስናአ ፡ ልጆችም ፡ የዓሣ ፡ በር ፡ ሠሩ ፤ ሰረ
ገሎቹን ፡ አኖሩ ፥ ሳንቃዎቹንም ፡ አቆሙ ፥
ቍልፎቹንና ፡ መወርወሪያዎቹንም ፡ አደረጉ ።
፬፤ በአጠገባቸውም ፡ የአቆስ ፡ ልጅ ፡ የኦርዮ ፡ ልጅ ፡
ሜሪሞት ፡ አደሰ ። በአጠገባቸውም ፡ የሜሴዜ
ቤል ፡ ልጅ ፡ የበራክያ ፡ ልጅ ፡ ሜሱላም ፡ አደሰ ።
በአጠገባቸውም ፡ የበዓና ፡ ልጅ ፡ ሳዶቅ ፡ አደሰ ።
፭፤ በአጠገባቸውም ፡ ቴቁሐውያን ፡ አደሱ ፤ ታላላ
ቆቻቸው ፡ ግን ፡ ለጌታቸው ፡ ሥራ ፡ አንገታቸ
ውን ፡ አላዋረዱም ።
፮፤ የፋሴሐ ፡ ልጅ ፡ ዮዳሄና ፡ የበሶድያ ፡ ልጅ ፡
ሜሱላም ፡ አሮጌውን ፡ በር ፡ አደሱ ፤ ሰረገሎ
ቹን ፡ አኖሩ ፥ ሳንቃዎቹንም ፡ አቆሙ ፥ ቍልፎ

፯፡ ቹንና፡መወርወሪያዎቹንም፡አደረጉ። በአጠ
ገባቸውም፡ገባዖናዊው፡መልጥያና፡ሜሮና
ታዊው፡ያዶን÷የወንዙም፡ማዶ፡አለቃ፡
ግዛት፡የሆኑ፡የገባዖንና፡የምጽጳ፡ሰዎች፡
፰፡ አደሱ። በአጠገባቸውም፡ወርቅ፡አንጥረ
ኛው፡የሐርሃያ፡ልጅ፡ዑዝኤል፡አደሰ። በአ
ጠገቡም፡ከሽቱ፡ቀማሚዎች፡የነበረ፡ሐና
ንያ፡አደሰ፤ እስከ፡ሰፊው፡ቅጥር፡ድረስ፡
፱፡ ኢየሩሳሌምን፡ጠገኑ። በአጠገባቸውም፡የኢ
የሩሳሌም፡ግዛት፡እኵሌታ፡አለቃ፡የሆር፡
፲፡ ልጅ፡ረፋያ፡አደሰ። በአጠገባቸውም፡የኤ
ርማፍ፡ልጅ፡ይዳያ፡በቤቱ፡አንጻር፡ያለውን፡
አደሰ። በአጠገቡም፡የአሰበንያ፡ልጅ፡ሐጡስ፡
፲፩፡ አደሰ። የካሪም፡ልጅ፡መልክያ÷የፈሐት፡
ሞዓብ፡ልጅም፡አሱብ፡ሌላውን፡ክፍልና፡
፲፪፡ የእቶኑን፡ግንብ፡አደሱ። በአጠገባቸውም፡
የኢየሩሳሌም፡ግዛት፡እኵሌታና፡የመንደሮ
ችዋ፡አለቃ፡የአሎኤስ፡ልጅ፡ሰሎም፡አደሰ።
፲፫፡ ሐኖንና፡የዛኖዋ፡ሰዎችም፡የሸለቆውን፡
በር፡አደሱ፤ ሠሩት÷ሳንቃዎቹንም፡አቆሙ÷
ቍልፎቹንና፡መወርወሪያዎቹንም፡አደረጉ፤
ደግሞም፡እስከ፡ጕድፍ፡መጣያው፡በር፡
ድረስ፡አንድ፡ሺህ፡ክንድ፡የሚሆን፡ቅጥር፡
ሠሩ።
፲፬፡ የቤትሐካሪምም፡ግዛት፡አለቃ፡የሬካብ፡
ልጅ፡መልክያ፡የጕድፍ፡መጣያውን፡በር፡
አደሰ፤ ሠራው÷ሳንቃዎቹንም፡አቆመ÷ቍል
ፎቹንና፡መወርወሪያዎቹንም፡አደረገ።
፲፭፡ የምጽጳም፡ግዛት፡አለቃ፡የኮልሖዜ፡ልጅ፡
ሰሎም፡የምንጩን፡በር፡አደሰ፤ ሠራው÷
ከደነውም÷ሳንቃዎቹንም፡አቆመ÷ቍልፎ
ቹንና፡መወርወሪያዎቹንም፡አደረገ፤ ከዳዊ
ትም፡ከተማ፡እስከሚወርደው፡ደረጃ፡ድረስ፡
በንጉሡ፡አትክልት፡አጠገብ፡ያለውን፡የሺ
፲፮፡ ላን፡መዋኛ፡ቅጥር፡ሠራ። ከእርሱም፡በኋላ፡
የቤትጹር፡ግዛት፡እኵሌታ፡አለቃ፡የዓዝ
ቡቅ፡ልጅ፡ነህምያ፡በዳዊት፡መቃብር፡አን
ጻር፡እስካለው፡ስፍራ÷እስከ፡ተሠራውም፡
መዋኛ÷እስከ፡ኃያላኑም፡ቤት፡ድረስ፡አደሰ።
፲፯፡ ከእርሱም፡በኋላ፡ሌዋውያንና፡የባኒ፡ልጅ፡
ሬሁም፡አደሱ። በአጠገባቸውም፡የቅዒላ፡
ግዛት፡እኵሌታ፡አለቃ፡ሐሸብያ፡ስለ፡ግዛቱ፡
፲፰፡ አደሰ። ከእርሱም፡በኋላ፡የቅዒላ፡ግዛት፡
እኵሌታ፡አለቃ፡የኤንሐዳድ፡ልጅ፡በዋይ፡
፲፱፡ ወንድሞቹም፡አደሱ። በአጠገቡም፡የምጽጳ፡
አለቃ፡የኢያሱ፡ልጅ፡ኤጽር፡በማዕዘኑ፡አጠ
ገብ፡በጦር፡መሣሪያ፡ቤት፡አንጻር፡ሌላውን፡
፳፡ ክፍል፡አደሰ። ከእርሱም፡በኋላ፡የዘባይ፡
ልጅ፡ባሮክ፡ከማዕዘኑ፡ጀምሮ፡እስከ፡ታላቁ፡
ካህን፡እስከ፡ኤልያሴብ፡ቤት፡መግቢያ፡ድረስ፡
፳፩፡ ሌላውን፡ክፍል፡ተግቶ፡አደሰ። ከእርሱም፡
በኋላ፡የአቆስ፡ልጅ፡የአርዮ፡ልጅ፡ሜሬ
ሞት፡ከኤልያሴብ፡ቤት፡መግቢያ፡ጀምሮ፡
እስከ፡ኤልያሴብ፡ቤት፡መጨረሻ፡ድረስ፡
፳፪፡ ሌላውን፡ክፍል፡አደሰ። ከእርሱም፡በኋላ፡
፳፫፡ የቈላው፡ሰዎች፡ካህናቱ፡አደሱ። ከእነር
ሱም፡በኋላ፡ብንያምና፡አሱብ፡በቤታቸው፡
አንጻር፡ያለውን፡አደሱ። ከእነርሱም፡በኋላ፡
የሐናንያ፡ልጅ፡የመዕሤያ፡ልጅ፡ዓዛርያስ፡
፳፬፡ በቤቱ፡አጠገብ፡ያለውን፡አደሰ። ከእርሱም፡
በኋላ፡የኤንሐደድ፡ልጅ፡ቢንዊ፡ከዓዛርያስ፡
ቤት፡ጀምሮ፡እስከ፡ማዕዘኑ፡ድረስ፡ሌላውን፡
፳፭፡ ክፍል፡አደሰ። የኡዛይ፡ልጅ፡ፋላል፡በማ
ዕዘኑ፡አንጻር፡ያለውንና፡በዘበኞች፡አደባ
ባይ፡አጠገብ፡ከላይኛው፡የንጉሡ፡ቤት፡
ወጥቶ፡የቆመውን፡ግንብ፡ሠራ። ከእርሱም፡
፳፮፡ በኋላ፡የፋሮስ፡ልጅ፡ፈዳያ፡ሠራ። ናታኒ
ምም፡በዖፌል፡በውኃው፡በር፡አንጻር፡በም
ሥራቅ፡በኩል፡ወጥቶ፡በቆመው፡ግንብ፡
አጠገብ፡እስካለው፡ስፍራ፡ድረስ፡ተቀመጡ።
፳፯፡ ከእርሱም፡በኋላ፡ቴቁሐውያን፡ወጥቶ፡በቆ
መው፡በታላቁ፡ግንብ፡አንጻር፡ያለውን፡
እስከ፡ዖፌል፡ቅጥር፡ድረስ፡ሌላውን፡ክፍል፡
አደሱ።
፳፰፡ ከፈረሱ፡በር፡በላይ፡ካህናቱ፡እያንዳንዳ
፳፱፡ ቸው፡በየቤታቸው፡አንጻር፡አደሱ። ከዚያ፡
በኋላ፡የኢሜር፡ልጅ፡ሳዶቅ፡በቤቱ፡አን
ጻር፡አደሰ። ከእርሱም፡በኋላ፡የምሥራ
ቁን፡በር፡ጠባቂ፡የሴኬንያ፡ልጅ፡ሸማያ፡
፴፡ አደሰ። ከእርሱ፡በኋላ፡የሰሌምያ፡ልጅ፡ሐና
ንያና፡የሴሌፍ፡ስድስተኛው፡ልጁ፡ሐኖን፡
ሌላውን፡ክፍል፡አደሱ። ከዚያም፡በኋላ፡
የበራክያ፡ልጅ፡ሜሱላም፡በጓዳው፡አንጻር፡
፴፩፡ ያለውን፡አደሰ። ከእርሱም፡በኋላ፡ከወርቅ፡
አንጥረኞቹ፡የነበረ፡መልክያ፡እስከ፡ናታኒ
ምና፡እስከ፡ነጋዴዎቹ፡ቤት፡ድረስ፡በሐሚ
ፍቃድ፡በር፡አንጻር፡ያለውን፡እስከ፡ማዕ
፴፪፡ ዘኑ፡መውጫ፡ድረስ፡አደሰ። ከማዕዘኑም፡
መውጫ፡ጀምረው፡እስከ፡በጉ፡በር፡ድረስ፡
ወርቅ፡አንጥረኞችና፡ነጋዴዎች፡አደሱ።

## ምዕራፍ፡፬።

፩፡ ሰንባላጥም፡ቅጥሩን፡እንደ፡ሠራን፡በሰማ፡
ጊዜ፡እጅግ፡ተቈጣ÷ተበሳጨም÷በአይሁ
፪፡ ድም፡አላገጠ። በወንድሞቹና፡በሰማርያ፡ሠራ
ዊትም፡ፊት፡— እነዚህ፡ደካሞች፡አይሁድ፡
የሚሠሩት፡ምንድር፡ነው? ይተዉላቸዋልን?
ይሠዋሉን? በአንድ፡ቀንስ፡ይጨርሳሉን?
የተቃጠለውንስ፡ድንጋይ፡ከፍርስራሹ፡መል
፫፡ ሰው፡ያድኑታልን? ብሎ፡ተናገረ። አሞናዊ
ውም፡ጦብያ፡በአጠገቡ፡ቆሞ፡— በድንጋይ፡
በሚሠሩት፡ቅጥራቸው፡ላይ፡ቀበሮ፡ቢመ
፬፡ ጣበት፡ያፈርሰዋል፡አለ። አምላካችን፡ሆይ÷
ተንቀናልና፡ስማ፤ ስድባቸውን፡በራሳቸው፡
ላይ፡መልስባቸው፤ በምርኮ፡አገር፡ለብዝበዛ፡
፭፡ አሳልፈህ፡ስጣቸው። በደላቸውንም፡አትክ
ደን÷ኃጢአታቸውም፡ከፊትህ፡አይደምሰስ፤
፮፡ በሠራተኞች፡ፊት፡አስቆጥተውሃልና። ቅጥ

ሩንም ፡ ሠራን ፤ ቅጥሩም ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ እኩ
ሌታው ፡ ድረስ ፡ ተጋጠመ ፤ የሕዝቡም ፡ ልብ ፡
ለሥራው ፡ ጨከነ ።

፯ ሰንባላጥና ፡ ጦብያም ፡ ዓረባውያንም ፡ አሞ
ናውያንም ፡ አሽዶዳውያንም ፡ የኢየሩሳሌም ፡
ቅጥር ፡ እየታደሰ ፡ እንደ ፡ ሄደ ÷ የፈረሰውም ፡
ሊጠገን ፡ እንደ ፡ ተጀመረ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡
፰ እጅግ ፡ ተቈጡ ። መጥተውም ፡ ኢየሩሳሌ
ምን ፡ ይወጉና ፡ ያሸብሩ ፡ ዘንድ ፡ ሁሉም ፡ በአ
፱ ንድነት ፡ ተማማሉ ። ወደ ፡ አምላካችንም ፡
ጸለይን ÷ ከእነርሱም ፡ የተነሣ ፡ በአንጻራቸው ፡
ተጠባባቂዎች ፡ በሌሊትና ፡ በቀን ፡ አደረግን ።
፲ ይሁዳም ፡— የተሸካሚዎች ፡ ኃይል ፡ ደከመ ÷
ፍርስራሹም ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ ቅጥሩንም ፡ እንሠራ ፡
፲፩ ዘንድ ፡ አንችልም ፡ አለ ። ጠላቶቻችንም ፡—
ወደ ፡ መካከላቸው ፡ እስክንመጣና ፡ እስክንገድ
ላቸው ፡ ድረስ ፡ ሥራቸውንም ፡ እስክናስተጓ
ጕል ፡ ድረስ ፡ አያውቁምና ፡ አያዩም ፡ አሉ ።
፲፪ በአጠገባቸውም ፡ የተቀመጡት ፡ አይሁድ ፡
መጥተው ፡— ከስፍራው ፡ ሁሉ ፡ ይመጡብናል ፡
፲፫ ብለው ፡ አሥር ፡ ጊዜ ፡ ነገሩን ። ከቅጥሩም ፡
በስተ ፡ ኋላ ፡ በኩል ፡ ባለው ፡ በታችኛው ፡
ስፍራ ፡ ሰይፋቸውን ፡ ጦራቸውንም ፡ ቀስታቸ
ውንም ፡ አስይዤ ፡ ሕዝቡን ፡ በየወገናቸው ፡
፲፬ አቆምኋቸው ። አይቼም ፡ ተነሣሁ ÷ ታላላቆቹ
ንና ፡ ሹማምቱንም ፡ የቀሩትንም ፡ ሕዝብ ፡—
አትፍሩአቸው ፤ ታላቁንና ፡ የተፈራውን ፡ ጌታ ፡
አስቡ ÷ ስለ ፡ ወንድሞቻችሁም ፡ ስለ ፡ ወንዶ
ችና ፡ ስለ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችሁም ፡ ስለ ፡ ሚስ
ቶቻችሁም ፡ ስለ ፡ ቤቶቻችሁም ፡ ተዋጉ ፡ አል
ኋቸው ።

፲፭ ጠላቶቻችንም ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ደረሰ
ልን ÷ እግዚአብሔርም ፡ ምክራቸውን ፡ ከንቱ ፡
እንዳደረገው ፡ ሰሙ ፤ እኛም ፡ ሁላችን ፡ ወደ ፡
ቅጥሩ ፡ እያንዳንዳችን ፡ ወደ ፡ ሥራችን ፡ ተመ
፲፮ ለስን ። ከዚያም ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እኵሌቶቹ ፡
ብላቴኖቼ ፡ ሥራ ፡ ይሠሩ ፡ ነበር ÷ እኵሌቶቹም ፡
ጋሻና ፡ ጦር ፡ ቀስትና ፡ ጥሩርም ፡ ይዘው ፡ ነበር ፤
አለቆቹም ፡ ከይሁዳ ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ በኋላ ፡
፲፯ ይቆሙ ፡ ነበር ። ቅጥሩንም ፡ የሚሠሩትና ፡ ተሸ
ካሚዎቹ ፡ በአንድ ፡ እጃቸው ፡ ይሠሩ ፡ ነበር ÷
በአንድ ፡ እጃቸውም ፡ የጦር ፡ መሣሪያቸውን ፡
፲፰ ይይዙ ፡ ነበር ። አናጢዎቹም ፡ ሁሉ ፡ እያንዳ
ንዱ ፡ ሰይፉን ፡ በወገቡ ፡ ታጥቆ ፡ ይሠራ ፡ ነበር ፤
ቀንደ ፡ መለከትም ፡ የሚነፋ ፡ በአጠገቤ ፡ ነበረ ።
፲፱ ታላላቆቹንና ፡ ሹማምቱን ፡ የቀሩትንም ፡
ሕዝብ ፡— ሥራው ፡ ታላቅና ፡ ሰፊ ፡ ነው ÷
እኛም ፡ በቅጥሩ ፡ ላይ ፡ ተበታትነናል ÷ አን
፳ ዱም ፡ ከሁለተኛው ፡ ርቆአል ፤ የቀንደ ፡ መለ
ከቱን ፡ ድምፅ ፡ ወደምትሰሙበት ፡ ስፍራ ፡ ወደ
ዚያ ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ ተሰብሰቡ ፤ አምላካችን ፡ ስለ ፡
እኛ ፡ ይዋጋል ፡ አልኋቸው ።

፳፩ ሥራውንም ፡ ሠራን ፡ ከማለዳ ፡ ወገግታም ፡
ጀምሮ ፡ ከዋክብት ፡ እስኪወጡ ፡ ድረስ ፡ እኩ
ሌቶቹ ፡ ጦር ፡ ይይዙ ፡ ነበር ። ፳፪ ደግሞም ፡ በዚያ ፡
ጊዜ ፡ ሕዝቡን ፡— ሁላችሁ ፡ ከብላቴኖቻችሁ ፡
ጋር ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ውስጥ ፡ እደሩ ፤ በሌሊ
ትም ፡ ጠባቂዎች ፡ ሁኑልን ÷ በቀንም ፡ ሥሩ ፡
አልኋቸው ። ፳፫ እኔና ፡ ወንድሞቼም ፡ ብላቴኖ
ቼም ፡ በኋላዬም ፡ የነበሩት ፡ ጠባቂዎች ፡ ልብ
ሳችንን ፡ አናወልቅም ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ በወንድሞቻቸውም ፡ በአይሁድ ፡ ላይ ፡
ትልቅ ፡ የሕዝቡና ፡ የሚስቶቻቸው ፡ ጩኸት ፡
፪ ሆነ ። አያሌዎቹም ፡— ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡
ልጆቻችን ፡ ብዙዎች ፡ ናቸው ፤ በልተንም ፡
በሕይወት ፡ እንድንኖር ፡ እህልን ፡ እንሸምት ፡
፫ ይሉ ፡ ነበር ። አያሌዎቹም ፡— ከራብ ፡ የተነሣ ፡
እህልን ፡ እንሸምት ፡ ዘንድ ፡ እርሻችንና ፡ ወይ
ናችንን ፡ ቤታችንንም ፡ አስይዘናል ፡ ይሉ ፡
፬ ነበር ። ሌሎቹም ፡— ለንጉሡ ፡ ግብር ፡ እርሻ
ችንንና ፡ ወይናችንን ፡ አስይዘን ፡ ገንዘብ ፡ ተበ
፭ ድረናል ፤ አሁንም ፡ ሥጋችን ፡ እንደ ፡ ወንድ
ሞቻችን ፡ ሥጋ ÷ ልጆቻችንም ፡ እንደ ፡ ልጆ
ቻቸው ፡ ናቸው ፤ እነሆም ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡
ልጆቻችን ፡ ባሪያዎች ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ሰጥተ
ናል ÷ ከሴቶችም ፡ ልጆቻችን ፡ ባሪያዎች ፡
ሆነው ፡ የሚኖሩ ፡ አሉ ፤ ታላላቆችም ፡ እርሻች
ንና ፡ ወይናችንን ፡ ይዘዋልና ፡ ልናድናቸው ፡
አንችልም ፡ ይሉ ፡ ነበር ።

፮ እኔም ፡ ጩኸታቸውንና ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ በሰ
፯ ማሁ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ተቈጣሁ ። በልቤም ፡ አሰ
ብሁ ÷ ታላላቆቹንና ፡ ሹማምቱንም ፡— ሁላ
ችሁ ፡ እያንዳንዳችሁ ፡ ወለድ ፡ ትወስዳላችሁ ፡
ብዬ ፡ ተጣላኋቸው ፤ ትልቅም ፡ ጉባኤ ፡ ሰበሰብ
፰ ሁባቸው ። እኔም ፡— ለአሕዛብ ፡ የተሸጡትን ፡
ወንድሞቻችንን ፡ አይሁድን ፡ በፈቃዳችን ፡
ተቤዠን ፤ እናንተስ ፡ ወንድሞቻችሁን ፡ ትሸጣላ
ችሁን ? እነርሱስ ፡ ለእኛ ፡ የተሸጡ ፡ ይሆናሉን ?
አልኋቸው ። እነርሱም ፡ ዝም ፡ አሉ ÷ መል
፱ ስም ፡ አላገኙም ። ደግሞም ፡ አልሁ ፡— የምታ
ደርጉት ፡ ነገር ፡ መልካም ፡ አይደለም ፤ ጠላቶ
ቻችን ፡ አሕዛብ ፡ እንዳይሰድቡን ፡ አምላካች
ንን ፡ በመፍራት ፡ ትሄዱ ፡ ዘንድ ፡ አይገባችሁ
፲ ምን ? እኔም ፡ ደግሞ ፡ ወንድሞቼም ፡ ብላቴኖ
ቼም ፡ ገንዘብና ፡ እህል ፡ ለእነርሱ ፡ አበድረናል ፤
እባካችሁ ÷ ይህን ፡ ወለድ ፡ እንተውላቸው ።
፲፩ እርሻቸውንና ፡ ወይናቸውን ፡ ወይራቸውንና ፡
ቤታቸውንም ፡ ከእነርሱም ፡ የወሰዳችሁትን ፡
ገንዘቡንና ፡ እህሉን ÷ ወይን ፡ ጠጁንና ፡ ዘይ
ቱን ፡ ከመቶ ፡ እጅ ፡ አንድ ፡ እጅ ፡ እባካችሁ ፡
፲፪ ዛሬ ፡ መልሱላቸው ። እነርሱም ፡— እንመልስላቸ
ዋለን ÷ ከእነርሱም ፡ ምንም ፡ አንሻም ፤ እንደ ፡
ተናገርህ ፡ እንዲሁ ፡ እናደርጋለን ፡ አሉ ። ካህ
ናቱንም ፡ ጠርቼ ፡ እንደዚህ ፡ ነገር ፡ ያደርጉ ፡
፲፫ ዘንድ ፡ አማልኋቸው ። ደግሞም ፡ ልብሴን ፡ አራ
ገፍሁና ፡— ይህን ፡ ነገር ፡ የማያደርገውን ፡ ሰው ፡

ከቤቱና ፡ ከሥራው ፡ እንዲሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያራግፈው ፤ እንዲሁም ፡ የተራገፈና ፡ ባዶ ፡ ይሁን ፡ አልሁ ። ጉባኤውም ፡ ሁሉ ፡— አሜን ፡ አሉ ÷ እግዚአብሔርንም ፡ አመሰገኑ ፤ ሕዝቡም ፡ እንደዚህ ፡ ነገር ፡ አደረጉ ።

፲፬ ንጉሡም ፡ በይሁዳ ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ ካዘዘኝ ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ ከንጉሡ ፡ ከአርጤክስስ ፡ ከሀያኛው ፡ ዓመት ፡ እስከ ፡ ሠላሳ ፡ ሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ እኔና ፡ ወንድሞቼ ፡ ለአለቃ ፡ የሚገባውን ፡ ስንቅ ፡ አልበላንም ። ፲፭ ከእኔ ፡ አስቀድመው ፡ የነበሩት ፡ አለቆች ፡ ግን ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ አክብደው ፡ ነበር ፤ ስለ ፡ እንጀራውና ፡ ስለ ፡ ወይኑ ፡ አርባ ፡ ሰቅል ፡ ብር ፡ ይወስዱ ፡ ነበር ፤ ሎሌዎቻቸውም ፡ ደግሞ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ይሠለጥኑ ፡ ነበር ፤ እኔ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ስለ ፡ ፈራሁ ፡ እንዲህ ፡ አላደረግሁም ። ፲፮ ደግሞም ፡ አጥብቄ ፡ የቅጥሩን ፡ ሥራ ፡ ሠራሁ ÷ እርሻም ፡ አልገዛንም ፤ ብላቴኖቼም ፡ ሁሉ ፡ ወደዚያው ፡ ወደ ፡ ሥራው ፡ ተሰበሰቡ ። ፲፯ ደግሞም ፡ በዙሪያችን ፡ ካሉት ፡ አሕዛብ ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ ከመጡት ፡ ሌላ ፡ ከአይሁድና ፡ ከሹማምቱ ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ሰዎች ፡ በገበታዬ ፡ ነበሩ ። ፲፰ ከወፎችም ፡ በቀር ፡ ለአንድ ፡ ቀን ፡ አንድ ፡ በሬና ፡ ስድስት ፡ የሰቡ ፡ በጎች ÷ በአሥር ፡ በአሥር ፡ ቀንም ፡ ብዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡ ይዘጋጅልኝ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አገዛዝ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ከብዶ ፡ ነበርና ፡ ለአለቃ ፡ የሚገባውን ፡ ስንቅ ፡ አልሻም ፡ ነበር ። ፲፱ አምላኬ ፡ ሆይ ÷ ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ያደረግሁትን ፡ ሁሉ ፡ ለበጎነት ፡ አስብልኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ቅጥሩን ፡ እንደ ፡ ሠራሁ ÷ ከፍራሹም ፡ አንዳች ፡ እንዳልቀረበት ፡ ሰንባላጥና ፡ ጦብያ ፡ ዓረባዊውም ፡ ጌሳም ፡ የቀሩትም ፡ ጠላቶቻችን ፡ ሰሙ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እስከዚያ ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡ በበሮቹ ፡ ውስጥ ፡ ሳንቃዎቹን ፡ አላቆምሁም ፡ ነበር ። ፪ ሰንባላጥና ፡ ጌሳም ፡— መጥተህ ፡ በኦኖ ፡ ቈላ ፡ ውስጥ ፡ ባሉት ፡ መንደሮች ፡ እንገናኝ ፡ ብለው ፡ ላኩብኝ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ ያደርጉብኝ ፡ ዘንድ ፡ ያስቡ ፡ ነበር ። ፫ እኔም ፡— ትልቅ ፡ ሥራ ፡ እሠራለሁ ÷ እወርድም ፡ ዘንድ ፡ አይቻለኝም ፤ ሥራውን ፡ ትቼ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ በመውረዴ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ሥራው ፡ ይታጐላል ? ብዬ ፡ መልእክተኞችን ፡ ላክሁባቸው ። ፬ እንዲህም ፡ ቃል ፡ አራት ፡ ጊዜ ፡ ላኩብኝ ፤ እኔም ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ ቃል ፡ መለስሁላቸው ። ፭ ሰንባላጥም ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ ጊዜ ፡ ብላቴናውን ፡ አምስተኛ ፡ ጊዜ ፡ ላከብኝ ፤ ፮ በእጁም ፡ ውስጥ ፡— አንተና ፡ አይሁድ ፡ ዓመፅ ፡ እንድታስቡ ÷ ስለዚህም ፡ ቅጥሩን ፡ እንድትሠራ ÷ ንጉሣቸውም ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ እንድትወድድ ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ተሰምቶአል ። ደግሞም ፡— ንጉሥ ፡ በይሁዳ ፡ አለ ፡ ብለው ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ይናገሩ ፡ ዘንድ ፡ ነቢያትን ፡ አቁመሃል ፤ ፯ አሁንም ፡ ለንጉሡ ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ያወሩለታል ፤ እንግዲህ ፡ መጥተህ ፡ በአንድነት ፡ እንማከር ፡ የሚል ፡ ክፍት ፡ ደብዳቤ ፡ ነበረ ። ፰ እኔም ፡— አንተ ፡ ከልብህ ፡ ፈጥረኸዋል ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ ተናገርኸው ፡ ነገር ፡ ምንም ፡ የለም ፡ ብዬ ፡ ላክሁበት ። ፱ እነርሱም ፡ ሁሉ ፡ ሥራው ፡ እንዳይፈጸም ፡— እጃቸው ፡ ይደክማል ፡ ብለው ፡ ያስፈራሩን ፡ ዘንድ ፡ ወደዱ ፤ አሁንም ÷ አምላክ ፡ ሆይ ÷ እጄን ፡ አበርታ ።

፲ እኔም ፡ ወደ ፡ መሔጣብኤል ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ድላያ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ሸማያ ፡ ቤት ፡ ገባሁ ፤ እርሱም ፡ ተዘግቶ ፡ ነበርና ፡— በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በመቅደሱ ፡ ውስጥ ፡ እንገናኝ ፡ የመቅደሱንም ፡ ደጆች ፡ እንዝጋ ፤ እነርሱ ፡ መጥተው ፡ ይገድሉሃልና ÷ በሌሊትም ፡ ይገድሉህ ፡ ዘንድ ፡ ይመጣሉና ፡ አለ ። ፲፩ እኔም ፡— እንደ ፡ እኔ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ የሸሽና ÷ ነፍሱንስ ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ የገባ ፡ ማን ፡ ነው ? እኔስ ፡ አልገባም ፡ አልሁት ። ፲፪ እግዚአብሔርም ፡ ልከት ፡ እንዳል ፡ ነበረ ÷ በእኔ ፡ ላይ ፡ ግን ፡ ትንቢት ፡ እንደ ፡ ተናገረ ÷ እነሆ ÷ አወቅሁ ፤ ጦብያና ፡ ሰንባላጥም ፡ ገዝተውት ፡ ነበር ። ፲፫ ይህንም ፡ ነገር ፡ አደርግና ፡ እበድል ፡ ዘንድ ÷ በእኔም ፡ ላይ ፡ ክፉት ፡ እንዲናገሩና ፡ እንዲያላግጡ ፡ ያስፈራራኝ ፡ ዘንድ ፡ ተገዝቶ ፡ ነበር ። ፲፬ አምላኬ ፡ ሆይ ÷ ስለዚህ ፡ ሥራቸው ፡ ጦብያንና ፡ ሰንባላጥን ፡ ያስፈራሩኝም ፡ ዘንድ ፡ የወደዱትን ፡ ነቢይቱን ፡ ኖዓድያን ፡ የቀሩትንም ፡ ነቢያት ፡ አስብ ።

፲፭ ቅጥሩም ፡ በኤሉል ፡ ወር ፡ በሀያ ፡ አምስተኛው ፡ ቀን ፡ በአምሳ ፡ ሁለት ፡ ቀን ፡ ውስጥ ፡ ተጨረሰ ። ፲፮ ጠላቶቻችንም ፡ ሁሉ ፡ ይህን ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ በዙሪያችን ፡ የነበሩ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ፈሩ ÷ በራሳቸውም ፡ አሳብ ፡ እጅግ ፡ ተዋረዱ ÷ ይህም ፡ ሥራ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተደረገ ፡ አወቁ ። ፲፯ ፲፰ ጦብያም ፡ የኤራ ፡ ልጅ ፡ የሴኬንያ ፡ አማች ፡ ስለ ፡ ነበረ ÷ ልጁም ፡ ይሆሐናን ፡ የቤራክያን ፡ ልጅ ፡ የሜሱላምን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ስላገባ ÷ በይሁዳ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተማምለው ፡ ነበርና ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ ብዙ ፡ የይሁዳ ፡ አለቆች ፡ ወደ ፡ ጦብያ ፡ ደብዳቤዎች ፡ ይልኩ ፡ ነበር ÷ የጦብያም ፡ ደብዳቤዎች ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ይመጡ ፡ ነበር ። ፲፱ ደግሞም ፡ በፊቴ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ መልካም ፡ ይናገሩ ፡ ነበር ÷ ቃሌንም ፡ ያወሩለት ፡ ነበር ፤ ጦብያም ፡ ሊያስፈራራኝ ፡ ደብዳቤዎችን ፡ ይልክ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ቅጥሩ ፡ ከተሠራ ፡ በኋላ ÷ ሳንቃዎቹንም ፡ ካቆምሁ ፡ በኋላ ÷ በረኞቹና ፡ መዘምራኑ ፡ ሌዋውያኑም ፡ ከተሾሙ ፡ በኋላ ÷ ፪ ወንድሜን ፡ አናኒንና ፡ የግንቡን ፡ አለቃ ፡ ሐና

ንያን፡በኢየሩሳሌም፡ላይ፡ሾምኋቸው ፤ እር
ሱም፡እውነተኛ፡ከሌሎቹም፡ይልቅ፡እግዚ
፫፡ አብሔርን፡የሚፈራ፡ሰው፡ነበረ ። እኔም፡—
ፀሐይ፡እስኪሞቅ፡ድረስ፡የኢየሩሳሌም፡
በሮች፡አይከፈቱ ፤ እነርሱም፡ቆመው፡ሳሉ፡
ደጆቹን፡ይዝጉ÷ይቈልፉም ፤ ከኢየሩሳሌ
ምም፡ሰዎች፡አንዳንዱን፡በየተራው፡አንዳ
ንዱንም፡በየቤቱ፡አንጻር፡ጠባቆችን፡አስቀ
፬፡ ምጡ፡አልኋቸው ። ከተማይቱም፡ሰፊና፡
ታላቅ፡ነበረች ፤ በውስጥዋ፡የነበሩ፡ሕዝብ፡
ግን፡ጥቂቶች፡ነበሩ÷ቤቶቹም፡አልተሠ
ሩም፡ነበር ።
፭፡ አምላኬም፡ታላቆቹንና፡ሹማምቱን፡ሕዝ
ቡንም፡ሰብስቤ፡እቈጥራቸው፡ዘንድ፡በልቤ፡
አደረገ ፤ አስቀድመው፡የመጡትን፡ሰዎች፡
የትውልድ፡መጽሐፋቸውን፡አገኘሁ÷በእር
፮፡ ሱም፡እንደዚህ፡ተጽፎ፡አገኘሁ ። የባቢሎን፡
ንጉሥ፡ናቡከደነፆር፡ከማረካቸው፡ምርኮኞች፡
ወደ፡ኢየሩሳሌምና፡ወደ፡ይሁዳ፡ወደ፡እየ
ከተማቸው፡የተመለሱት፡የአገር፡ልጆች፡
፯፡ እነዚህ፡ናቸው ። ከዘሩባቤል÷ከኢያሱ÷ከነ
ህምያ÷ከአዛርያስ÷ከረዓምያ÷ከነሐማኒ÷ከመ
ርዶክዮስ÷ከበላሳን÷ከሚስጴሬት÷ከበጉ
ዋይ÷ከነሑም÷ከበዓና፡ጋር፡መጡ ።
፰፡ የእስራኤልም፡ሕዝብ፡ሰዎች፡ቍጥር፡ይህ፡
ነው ፤ የፋሮስ፡ልጆች÷ሁለት፡ሺህ፡መቶ፡
፱፡ ሰባ፡ሁለት ። የሰፋጥያስ፡ልጆች÷ሦስት፡መቶ፡
፲፡ ሰባ፡ሁለት ። የኤራ፡ልጆች÷ስድስት፡መቶ፡
፲፩፡ አምሳ፡ሁለት ። ከኢያሱና፡ከኢዮአብ፡ልጆች፡
የሆኑ፡የፈሐት፡ሞዓብ፡ልጆች÷ሁለት፡ሺህ፡
፲፪፡ ስምንት፡መቶ፡አሥራ፡ስምንት ። የኤላም፡
ልጆች÷ሺህ፡ሁለት፡መቶ፡አምሳ፡አራት ።
፲፫፡ የዛቱዕ፡ልጆች÷ስምንት፡መቶ፡አርባ፡አም
፲፬፡ ስት ። የዘካይ፡ልጆች÷ሰባት፡መቶ፡ስድሳ ።
፲፭፡ የቢንዊ፡ልጆች÷ስድስት፡መቶ፡አርባ፡ስም
፲፮፡ ንት ። የቤባይ፡ልጆች÷ስድስት፡መቶ፡ሀያ፡
፲፯፡ ስምንት ። የዓዝጋድ፡ልጆች÷ሁለት፡ሺህ፡
፲፰፡ ሦስት፡መቶ፡ሀያ፡ሁለት ። የአዶኒቃም፡
፲፱፡ ልጆች÷ስድስት፡መቶ፡ስድሳ፡ሰባት ። የበጉ
ዋይ፡ልጆች÷ሁለት፡ሺህ፡ስድሳ፡ሰባት ።
፳፡ የዓዲን፡ልጆች÷ስድስት፡መቶ፡አምሳ፡አም
፳፩፡ ስት ። የሕዝቅያስ፡ወገን፡የአጤር፡ልጆች÷
፳፪፡ ዘጠና፡ስምንት ። የሐሱም፡ልጆች÷ሦስት፡
፳፫፡ መቶ፡ሀያ፡ስምንት ። የቤሳይ፡ልጆች÷ሦስት፡
፳፬፡ መቶ፡ሀያ፡አራት ። የሐሪፍ፡ልጆች÷መቶ፡
፳፭፡ አሥራ፡ሁለት ። የገባዖን፡ልጆች÷ዘጠና፡
፳፮፡ አምስት ። የቤተ፡ልሔምና፡የነጦፋ፡ሰዎች÷
፳፯፡ መቶ፡ሰማንያ፡ስምንት ። የዓናቶት፡ሰዎች÷
፳፰፡ መቶ፡ሀያ፡ስምንት ። የቤትዓዝሞት፡ሰዎች÷
፳፱፡ አርባ፡ሁለት ። የቂርያትይዓሪምና፡የከፊራ፡
የብኤሮትም፡ሰዎች÷ሰባት፡መቶ፡አርባ፡
፴፡ ሦስት ። የራማና፡የጌባ፡ሰዎች÷ስድስት፡
፴፩፡ መቶ፡ሀያ፡አንድ ። የማክማስ፡ሰዎች÷መቶ፡
፴፪፡ ሀያ፡ሁለት ። የቤቴልና፡የጋይ፡ሰዎች÷መቶ፡
፴፫፡ ሀያ፡ሦስት ። የሁለተኛው፡ናባው፡ሰዎች÷
፴፬፡ አምሳ፡ሁለት ። የሁለተኛው፡ኤላም፡ልጆች÷
፴፭፡ ሺህ፡ሁለት፡መቶ፡አምሳ፡አራት ። የካሪም፡
፴፮፡ ልጆች÷ሦስት፡መቶ፡ሀያ ። የኢያሪኮ፡ልጆች÷
፴፯፡ ሦስት፡መቶ፡አርባ፡አምስት ። የሎድና፡የሐ
ዲድ፡የአኖም፡ልጆች÷ሰባት፡መቶ፡ሀያ፡
፴፰፡ አንድ ። የሴናዓ፡ልጆች÷ሦስት፡ሺህ፡ዘጠኝ፡
መቶ፡ሠላሳ ።
፴፱፡ ካህናቱ ፤ ከኢያሱ፡ወገን፡የዮዳኤ፡ልጆች÷
፵፡ ዘጠኝ፡መቶ፡ሰባ፡ሦስት ። የኢሜር፡ልጆች÷
፵፩፡ ሺህ፡አምሳ፡ሁለት ። የፋስኮር፡ልጆች÷
፵፪፡ ሺህ፡ሁለት፡መቶ፡አርባ፡ሰባት ። የካሪም፡
ልጆች÷ሺህ፡አሥራ፡ሰባት ።
፵፫፡ ሌዋውያኑ ፤ ከሆዳይዋ፡ወገን፡የኢያሱና፡
የቀድምኤል፡ልጆች÷ሰባ፡አራት ።
፵፬፡ መዘምራኑ ፤ የአሳፍ፡ልጆች÷መቶ፡አርባ፡
ስምንት ።
፵፭፡ በረኞቹ ፤ የሰሎም፡ልጆች÷የአጤር፡
ልጆች÷የጤልሞን፡ልጆች÷የዓቁብ፡ልጆች÷
የሐጢጣ፡ልጆች÷የሰባይ፡ልጆች÷መቶ፡
ሠላሳ፡ስምንት ።
፵፮፡ ናታኒም ፤ የሲሐ፡ልጆች÷የሐሡፋ፡ልጆች÷
፵፯፡ የጠብዖት፡ልጆች÷የኬራስ፡ልጆች÷የሲዓ፡
፵፰፡ ልጆች÷የፋዶን፡ልጆች÷የልባና፡ልጆች÷
፵፱፡ የአጋበ፡ልጆች÷የሰምላይ፡ልጆች÷የሐናን፡
ልጆች÷የጌዴል፡ልጆች÷የጋሐር፡ልጆች÷
፶፡ የራያ፡ልጆች÷የረአሶን፡ልጆች÷የኔቆዳ፡
፶፩፡ ልጆች÷የጋሴም፡ልጆች÷የዖዛ፡ልጆች÷የፋ
፶፪፡ ሴሐ፡ልጆች÷የቤሳይ፡ልጆች÷የምዑናው
፶፫፡ ያን፡ልጆች÷የንፋሰሲም፡ልጆች÷የበቅቡቅ፡
ልጆች÷የሐቀፋ፡ልጆች÷የሐርሑር፡ልጆች÷
፶፬፡ የበስሎት፡ልጆች÷የምሒዳ፡ልጆች÷የሐ
፶፭፡ ርሻ፡ልጆች÷የበርቆስ፡ልጆች÷የሲሣራ፡
፶፮፡ ልጆች÷የቴማ፡ልጆች÷የንስያ፡ልጆች÷
የሐጢፋ፡ልጆች ።
፶፯፡ የሰሎሞን፡ባሪያዎች፡ልጆች ፤ የሶጣይ፡
ልጆች÷የሶፌሬት፡ልጆች÷የፍሩዳ፡ልጆች÷
፶፰፡ የየዕላ፡ልጆች÷የደርቆን፡ልጆች÷የጌዴል፡
፶፱፡ ልጆች÷የሰፋጥያስ፡ልጆች÷የሐጢል፡
ልጆች÷የፈከራት፡ልጆች÷የሐፂበይም፡
፷፡ ልጆች÷የአሞን፡ልጆች ። ናታኒም፡ሁሉና፡
የሰሎሞን፡ባሪያዎች፡ልጆች፡ሦስት፡መቶ፡
ዘጠና፡ሁለት፡ነበሩ ።
፷፩፡ ከቴልሚላ÷ከቴላሬሳ÷ከክሩብ÷ከአዳን÷
ከኢሜር፡የወጡ፡እነዚህ፡ናቸው ፤ ነገር፡ግን፡
የአባቶቻቸውን፡ቤቶችና፡ዘራቸውን፡ወይም፡
ከእስራኤል፡ወገን፡መሆናቸውን፡ያስታውቁ፡
፷፪፡ ዘንድ፡አልቻሉም ፤ የዳላያ፡ልጆች÷የጦ
ብያ፡ልጆች÷የኔቆዳ፡ልጆች÷ስድስት፡
፷፫፡ መቶ፡አርባ፡ሁለት ። ከካህናቱም፡የኤብያ፡
ልጆች÷የአቆስ፡ልጆች÷ከገለዓዳዊው፡ከቤ
ርዜሊ፡ልጆች፡ሚስት፡ያገባ፡በስሙም፡የተ
፷፬፡ ጠራ፡የቤርዜሊ፡ልጆች ። እነዚህ፡በትው
ልድ፡መጽሐፍ፡ትውልዳቸውን፡ፈለጉ÷

ነገር፡ግን፡አልተገኘም፤ ከክህነትም፡ተከለ
ከሉ። ፷፭ ሐቴርሰታም፦ በኡሪምና፡በቱሚም፡
የሚፈርድ፡ካህን፡እስኪነሣ፡ድረስ፡ከተቀደ
ሰው፡ነገር፡አትበሉም፡አላቸው።

፷፮፡፷፯ ሰባት፡ሺህ፡ሦስት፡መቶ፡ሠላሳ፡ሰባት፡ከነ
በሩ፡ከሎሌዎቻቸውና፡ከገረዶቻቸው፡ሌላ፡
ጉባኤው፡ሁሉ፡አርባ፡ሁለት፡ሺህ፡ሦስት፡
መቶ፡ስድሳ፡ነበሩ፤ ሁለቱ፡መቶም፡አርባ፡
አምስት፡ወንዶችና፡ሴቶች፡መዘምራን፡
ነበሩአቸው። ፷፰ ፈረሶቻቸውም፡ሰባት፡መቶ፡
ሠላሳ፡ስድስት፥ በቅሎቻቸውም፡ሁለት፡
መቶ፡አርባ፡አምስት፥ ፷፱ ግመሎቻቸውም፡
አራት፡መቶ፡ሠላሳ፡አምስት፥ አህዮቻቸ
ውም፡ስድስት፡ሺህ፡ሰባት፡መቶ፡ሀያ፡
ነበሩ።

፸ ከአባቶች፡ቤቶች፡አለቆችም፡አያሌዎቹ፡
ሰዎች፡ስለ፡ሥራው፡ስጦታ፡ሰጡ። ሐቴር
ሰታም፡አንድ፡ሺህ፡የወርቅ፡ዳሪክ፥አምሳም፡
ድስቶች፥አምስት፡መቶ፡ሠላሳም፡የካህናት፡
ልብስ፡በቤተ፡መዛግብት፡ውስጥ፡ሰጠ።
፸፩ ከአባቶች፡ቤቶች፡አለቆችም፡አያሌዎቹ፡
በሥራው፡ቤተ፡መዛግብት፡ውስጥ፡ሀያ፡
ሺህ፡የወርቅ፡ዳሪክ፥ሁለት፡ሺህ፡ሁለት፡
፸፪ መቶም፡ምናን፡ብር፡ሰጡ። የቀሩትም፡
ሕዝብ፡የሰጡት፡ሀያ፡ሺህ፡የወርቅ፡ዳሪክና፡
ሁለት፡ሺህ፡ምናን፡ብር፥ስድሳ፡ሰባትም፡
የካህናት፡ልብስ፡ነበረ።

፸፫ ካህናቱና፡ሌዋውያኑም፥በረኞቹና፡መዘም
ራኑም፡ከሕዝቡም፡አያሌዎቹ፥ናታኒምም፥
እስራኤልም፡ሁሉ፡በከተሞቻቸው፡ተቀ
መጡ።

## ምዕራፍ፡፰።

፩ ሰባተኛውም፡ወር፡በደረሰ፡ጊዜ፡የእስራ
ኤል፡ልጆች፡በከተሞቻቸው፡ነበሩ። ሕዝ
ቡም፡ሁሉ፡በውኃው፡በር፡ፊት፡ወዳለው፡
አደባባይ፡እንደ፡አንድ፡ሰው፡ሆነው፡ተሰበ
ሰቡ፤ እግዚአብሔርም፡ለእስራኤል፡ያዘዘ
ውን፡የሙሴን፡ሕግ፡መጽሐፍ፡ያመጣ፡ዘንድ፡
፪ ጸሐፊውን፡ዕዝራን፡ተናገሩት። ካህኑም፡
ዕዝራ፡በሰባተኛው፡ወር፡በመጀመሪያው፡
ቀን፡ሕጉን፡በማኅበሩ፡በወንዶችና፡በሴቶች፡
አስተውለውም፡በሚሰሙት፡ሁሉ፡ፊት፡
፫ አመጣው። በውኃውም፡በር፡ፊት፡ባለው፡
አደባባይ፡ላይ፡ቆሞ፥ወንዶችና፡ሴቶች፡
የሚያስተውሉም፡ሲሰሙ፥ከማለዳ፡ጀምሮ፡
እስከ፡ቀትር፡ድረስ፡አነበበው፤ የሕዝቡም፡
ሁሉ፡ጆሮ፡የሕጉን፡መጽሐፍ፡ለመስማት፡
፬ ያደምጥ፡ነበር። ጸሐፊውም፡ዕዝራ፡ስለዚህ፡
ነገር፡በተሠራ፡በእንጨት፡መረባርብ፡ላይ፡
ቆሞ፡ነበር፤ በአጠገቡ፡መቲትያ፥ሽማዕ፥
ዓናያ፥ኦርዮ፥ኬልቅያስ፥መዕሤያ፡በቀኙ፡
በኩል፥ፈዳያ፥ሚሳኤል፥መልክያ፥ሐሱም፥
ሐሽበዳና፥ዘካርያስ፥ሜሱላም፡በግራው፡
በኩል፡ቆመው፡ነበር። ፭ ዕዝራም፡በሕዝቡ፡
ሁሉ፡ላይ፡ከፍ፡ብሎ፡ሕዝቡ፡ሁሉ፡እያዩ፡
መጽሐፉን፡ገለጠ፤ በገለጠውም፡ጊዜ፡ሕዝቡ፡
ሁሉ፡ቆሙ። ፮ ዕዝራም፡ታላቁን፡አምላክ፡
እግዚአብሔርን፡ባረከ፤ ሕዝቡም፡ሁሉ፡እጃ
ቸውን፡እየዘረጉ፦ አሜን፥አሜን፡ብለው፡
መለሱ። ራሳቸውንም፡አዘነበሉ፥በግምባራ
ቸውም፡ተደፍተው፡ለእግዚአብሔር፡ሰገዱ።
፯ ደግሞ፡ኢያሱና፡ባኒ፥ሰራብያ፥ያሚን፥
ዓቁብ፥ሳባታይ፥ሆዲያ፥መዕሤያ፥ቆሊጣስ፥
ዓዛርያስ፥ዮዛባት፥ሐናን፥ፌልያ፥ሌዋውያ
ኑም፡ሕጉን፡ያስተውሉ፡ዘንድ፡ሕዝቡን፡
ያስተምሩ፡ነበር፤ ሕዝቡም፡በየስፍራቸው፡
ቆመው፡ነበር። ፰ የእግዚአብሔርንም፡ሕግ፡
መጽሐፍ፡አነበቡ፤ ዕዝራም፡እግዚአብሔ
ርን፡ማወቅ፡ያስተምርና፡ያስታውቅ፡ነበር፥
ሕዝቡም፡የሚነበበውን፡ያስተውሉ፡ነበር።

፱ ሐቴርሰታ፡ነህምያም፡ጸሐፊውም፡ካህኑ፡
ዕዝራ፡ሕዝቡንም፡የሚያስተምሩ፡ሌዋው
ያን፡ሕዝቡን፡ሁሉ፦ ዛሬ፡ለአምላካችን፡
ለእግዚአብሔር፡የተቀደሰ፡ቀን፡ነው፤ አታ
ልቅሱ፡እንባም፡አታፍስሱ፡አሉአቸው፤
ሕዝቡ፡ሁሉ፡የሕጉን፡ቃል፡በሰሙ፡ጊዜ፡
ያለቅሱ፡ነበርና። ፲ እርሱም፦ ሂዱ፥የሰባው
ንም፡ብሉ፥ጣፋጩንም፡ጠጡ፥ለእነዚያም፡
ላልተዘጋጀላቸው፡እድል፡ፈንታቸውን፡
ስደዱ፤ ዛሬ፡ለጌታችን፡የተቀደሰ፡ቀን፡ነው፤
የእግዚአብሔርም፡ደስታ፡ኃይላችሁ፡ነውና፡
አትዘኑ፡አላቸው። ፲፩ ሌዋውያንም፦ ቀኑ፡የተ
ቀደሰ፡ነውና፡ዝም፡በሉ፥አትዘኑም፡ብለው፡
ሕዝቡን፡ሁሉ፡ጸጥ፡ያደርጉ፡ነበር። ፲፪ ሕዝ
ቡም፡ሁሉ፡የተነገረላቸውን፡ቃል፡አስተው
ለዋልና፡ሊበሉና፡ሊጠጡ፡እድል፡ፈንታም፡
ሊሰድዱ፡ደስታም፡ሊያደርጉ፡ሄዱ።

፲፫ በሁለተኛውም፡ቀን፡ከሕዝቡ፡ሁሉ፡የአባ
ቶች፡ቤቶች፡አለቆች፡ካህናቱም፡ሌዋውያ
ኑም፡የሕጉን፡ቃል፡ይተረጕምላቸው፡ዘንድ፡
ወደ፡ጸሐፊው፡ወደ፡ዕዝራ፡ተሰበሰቡ።
፲፬፡፲፭ በሰባተኛውም፡ወር፡ባለው፡በዓል፡የእስራ
ኤል፡ልጆች፡በዳስ፡ይቀመጡ፡ዘንድ፡በከተሞ
ቻቸውና፡በኢየሩሳሌምም፦ ወደ፡ተራራ፡
ሂዱ፤ የዘይትና፡የበረሀ፡ወይራ፡የባርሰነትም፡
የዘንባባም፡የለመለመውን፡ዛፍ፡ቅርንጫፍ፡
አምጡ፥እንደ፡ተጻፈውም፡ዳሶችን፡ሥሩ፡
ብለው፡ይናገሩ፡ያውጁም፡ዘንድ፡እግዚአብ
ሔር፡በሙሴ፡እጅ፡እንዳዘዘ፡በሕጉ፡ውስጥ፡
ተጽፎ፡አገኙ። ፲፮ ሕዝቡም፡ወጥተው፡አመጡ፤
እያንዳንዱም፡በቤቱ፡ሰገነት፡ላይ፥በአደባ
ባዩም፡ላይ፥በእግዚአብሔርም፡ቤት፡አደባ
ባዩ፡ላይ፥በውኃውም፡በር፡አደባባይና፡በኤ
ፍሬም፡በር፡አደባባይ፡ላይ፡ዳስ፡ሠራ።
፲፯ ከምርኮም፡የተመለሱት፡ማኅበር፡ሁሉ፡ዳስ፡
ሠሩ፥በዳሱም፡ውስጥ፡ተቀመጡ። ከነዌም፡
ልጅ፡ከኢያሱ፡ዘመን፡ጀምሮ፡እስከዚያ፡

ቀን ፡ ድረስ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡
ያለ ፡ አላደረጉም ፡ ነበር ። እጅግም ፡ ታላቅ ፡
፲፰ ደስታ ፡ ሆነ ። ከመጀመሪያውም ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡
እስከ ፡ መጨረሻው ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ ያነብብ ፡
ነበር ። በዓሉን ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ አደረጉ ፤
በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ የተቀ
ደሰ ፡ ጉባኤ ፡ ነበረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ በዚህም ፡ ወር ፡ በሀያ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ የእ
ስራኤል ፡ ልጆች ፡ ጾመው ፥ ማቅም ፡ ለብሰው ፥
፪ በላያቸውም ፡ ትቢያ ፡ ነስንሰው ፡ ተከማቹ ። የእ
ስራኤልም ፡ ዘር ፡ ከእንግዶች ፡ ሁሉ ፡ ራሳቸ
ውን ፡ ለዩ ፥ ቆመውም ፡ ኃጢአታቸውንና ፡
፫ የአባቶቻቸውን ፡ ኃጢአት ፡ ተናዘዙ ። በየስፍ
ራቸውም ፡ ቆመው ፡ የአምላካቸውን ፡ የእግዚ
አብሔርን ፡ የሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ የቀን ፡ ሩብ ፡
ያህል ፡ አነበቡ ፤ ሦስት ፡ የቀን ፡ ሩብም ፡ ያህል ፡
ተናዘዙ ፥ ለአምላካቸው ፡ ለእግዚአብሔርም ፡
፬ ሰገዱ ። ሌዋውያኑም ፡ ኢያሱና ፡ ባኒ ፥ ቀድ
ምኤል ፥ ሰበንያ ፥ ቡኒ ፥ ሰራብያ ፥ ባኒ ፥ ክናኒ ፡
በደረጃዎች ፡ ላይ ፡ ቆመው ፡ ወደ ፡ አምላካቸው ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ጮኹ ።
፭ ሌዋውያኑም ፡ ኢያሱ ፥ ቀድምኤል ፥ ባኒ ፥
አሰበንያ ፥ ሰራብያ ፥ ሆዲያ ፥ ሰበንያ ፥ ፈታያ ፡
እንዲህ ፡ አሉ ፡— ቆማችሁ ፡ ከዘላለም ፡ እስከ ፡
ዘላለም ፡ አምላካችንን ፡ እግዚአብሔርን ፡
ባርኩ ። እንዲህም ፡ በሉ ፡— በበረከትና ፡ በም
ስጋና ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያለው ፡ ክቡር ፡
፮ ስምህ ፡ ይባረክ ። አንተ ፡ ብቻ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ነህ ፤ ሰማዩንና ፡ የሰማያት ፡ ሰማይን ፡
ሠራዊታቸውንም ፡ ሁሉ ፥ ምድሩንና ፡ በእር
ስዋ ፡ ላይ ፡ ያሉትን ፡ ሁሉ ፥ ባሕሮቹንና ፡ በእ
ነርሱ ፡ ውስጥ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ፈጥረሃል ፥
ሁሉንም ፡ ሕያው ፡ አድርገኸዋል ፤ የሰማዩም ፡
፯ ሠራዊት ፡ ለአንተ ፡ ይሰግዳሉ ። አንተ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ነህ ፤ አብራምን ፡ መረ
ጥህ ፥ ከዑር ፡ ከላውዴዎንም ፡ አወጣኸው ፥
፰ ስሙንም ፡ አብርሃም ፡ አልኸው ፤ ልቡም ፡
በፊትህ ፡ የታመነ ፡ ሆኖ ፡ አገኘኸው ፤ የከነዓና
ዊውንና ፡ የኬጢያዊውን ፡ የአሞራዊውንም ፡
የፌርዛዊውንም ፡ የኢያቡሳዊውንም ፡ የጌርጌ
ሳዊውንም ፡ ምድር ፡ ለእርሱና ፡ ለዘሩ ፡ ትሰጥ ፡
ዘንድ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረ
ግህ ፤ አንተም ፡ ጻድቅ ፡ ነህና ፡ ቃልህን ፡ ፈጸ
ምህ ።
፱ በግብጽም ፡ ሳሉ ፡ የአባታችንን ፡ መከራ ፡
አየህ ፥ በኤርትራ ፡ ባሕርም ፡ ሳሉ ፡ ጩኸታቸ
፲ ውን ፡ ሰማህ ፤ እንደ ፡ ታበዩባቸውም ፡ አው
ቀህ ፡ ነበርና ፡ በፈርዖንና ፡ በባሪያዎቹ ፡ ሁሉ ፡
በምድሩም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ምልክትና ፡
ተአምራት ፡ አሳየህ ፤ ዛሬም ፡ እንደ ፡ ሆነው ፡
፲፩ ስምህን ፡ አስጠራህ ። ከፊታቸውም ፡ ባሕሩን ፡
ከፈልህ ፥ በባሕሩም ፡ መካከል ፡ በደረቅ ፡ አለፉ ፤
ጠላቶቻቸውን ፡ ግን ፡ ድንጋይ ፡ ለጥልቅ ፡ ውኃ ፡
እንዲጣል ፡ በቀላይ ፡ ውስጥ ፡ ጣልሃቸው ።
፲፪ የሚሄዱበትንም ፡ መንገድ ፡ ታበራላቸው ፡
ዘንድ ፡ በቀን ፡ በደመና ፡ ዓምድ ፥ በሌሊትም ፡
፲፫ በእሳት ፡ ዓምድ ፡ መራሃቸው ። ወደ ፡ ሲናም ፡
ተራራ ፡ ወረድህ ፥ ከሰማይም ፡ ተናገርሃቸው ፤
ቅኑን ፡ ፍርድና ፡ እውነቱን ፡ ሕግ ፡ መልካሙ
፲፬ ንም ፡ ሥርዓትና ፡ ትእዛዝ ፡ ሰጠሃቸው ፤ የተቀ
ደሰውንም ፡ ሰንበትህን ፡ አስታወቅሃቸው ፥
ትእዛዝንና ፡ ሥርዓትን ፡ ሕግንም ፡ በባሪያህ ፡
፲፭ በሙሴ ፡ እጅ ፡ አዘዝሃቸው ። ለራባቸውም ፡ ከሰ
ማይ ፡ እንጀራ ፡ ሰጠሃቸው ፥ ለጥማታቸውም ፡
ከዓለቱ ፡ ውኃ ፡ አመጣህላቸው ፤ ወደ ፡ ማልህ
ላቸውም ፡ ምድር ፡ ገብተው ፡ ይወርሱ ፡ ዘንድ ፡
አዘዝሃቸው ።
፲፮ ነገር ፡ ግን ፡ እነርሱና ፡ አባቶቻችን ፡ ታበዩ ፥
አንገታቸውንም ፡ አደነደኑ ፥ ትእዛዝህንም ፡
፲፯ አልሰሙም ፥ ለመስማትም ፡ እንቢ ፡ አሉ ፥
ያደረግህላቸውንም ፡ ተአምራት ፡ አላሰቡም ፤
አንገታቸውንም ፡ አደነደኑ ፥ በዓመፃቸውም ፡
ወደ ፡ ባርነታቸው ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ አለቃ ፡
አደረጉ ፤ አንተ ፡ ግን ፡ ይቅር ፡ ባይ ፥ ቸርና ፡
መሐሪ ፡ አምላክ ፥ ለቍጣም ፡ የምትዘገይ ፥ ምሕ
ረትንም ፡ የምታበዛ ፡ ነህ ፥ አልተውሃቸውም ።
፲፰ ቀልጦ ፡ የተሠራውንም ፡ እምቦሳ ፡ አድርገው ፡—
ከግብጽ ፡ ያወጣህ ፡ አምላክህ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ባሉ ፡
፲፱ ጊዜ ፥ እጅግም ፡ ባስቈጡህ ፡ ጊዜ ፥ አንተ ፡
በምሕረትህ ፡ ብዛት ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ አልተው
ሃቸውም ፤ በመንገድም ፡ ይመራቸው ፡ ዘንድ ፡
የደመና ፡ ዓምድ ፡ በቀን ፥ የሚሄዱበትንም ፡
መንገድ ፡ ያበራላቸው ፡ ዘንድ ፡ የእሳት ፡ ዓምድ ፡
፳ በሌሊት ፡ ከእነርሱ ፡ አልራቀም ። ያስተምራ
ቸውም ፡ ዘንድ ፡ መልካሙን ፡ መንፈስህን ፡
ሰጠሃቸው ፥ መናህንም ፡ ከአፋቸው ፡ አልከለከ
ልህም ፥ ለጥማታቸውም ፡ ውኃ ፡ ሰጠሃቸው ።
፳፩ አርባ ፡ ዓመትም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ መገብሃቸው ፥
ምንም ፡ አላጡም ፤ ልብሳቸውም ፡ አላረጀም ፥
እግራቸውም ፡ አላበጠም ።
፳፪ መንግሥታትንና ፡ አሕዛብን ፡ ከፍለህ ፡ ሰጠሃ
ቸው ፤ የሐሴቦንን ፡ ንጉሥ ፡ የሴዎንን ፡ ምድር ፥
የባሳንንም ፡ ንጉሥ ፡ የዐግን ፡ ምድር ፡ ወረሱ ።
፳፫ ልጆቻቸውንም ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከዋክብት ፡
አበዛህ ፤ ይገቡና ፡ ይወርሱ ፡ ዘንድ ፡ ለአባቶቻ
ቸው ፡ ወደ ፡ ተናገርህላቸውም ፡ ምድር ፡ አገባ
፳፬ ሃቸው ። ልጆቹም ፡ ገብተው ፡ ምድሩን ፡ ወረሱ ፥
የምድሩን ፡ ሰዎች ፡ ከነዓናውያንን ፡ በፊታቸው ፡
አዋረድህ ፤ የሚወድዱትንም ፡ ነገር ፡ ያደርጉብ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ እነርሱንና ፡ ነገሥታቶቻቸውን ፡
የምድሩንም ፡ አሕዛብ ፡ በእጃቸው ፡ አሳልፈህ ፡
፳፭ ሰጠሃቸው ። ምሽጎቹንም ፡ ከተሞች ፡ የሰባው
ንም ፡ ምድር ፡ወሰዱ ፤ መልካምን ፡ ነገር ፡ የሞ
ሉትን ፡ ቤቶች ፥ የተማሱትንም ፡ ጕድጓዶች ፥
ወይኖቹንና ፡ ወይራዎቹን ፡ ብዙዎቹንም ፡ የፍሬ ፡

ዛፎች ፡ ወረሱ ፤ በሉም ፥ ጠገቡም ፥ ወፈሩም ፥ በታላቅ ፡ በጎነትህም ፡ ደስ ፡ አላቸው ።

፳፮ ነገር ፡ ግን ፡ እንቢተኞች ፡ ነበሩ ፥ ዐመፁብህም ፥ ሕግህንም ፡ ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ጣሉት ፤ ወደ ፡ አንተም ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ የመሰከሩባቸውን ፡ ነቢያትህን ፡ ገደሉ ፥ እጅግም ፡ አስቈጡህ ። ፳፯ ስለዚህ ፡ ለጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡ አሳልፈህ ፡ ሰጠሃቸው ፥ አስጨነቁአቸውም ፤ በመከራቸውም ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኹ ፥ ከሰማይም ፡ ሰማሃቸው ፤ እንደ ፡ ምሕረትህም ፡ ብዛት ፡ ከጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡ ያዳኑአቸውን ፡ ታዳጊዎችን ፡ ሰጠሃቸው ። ፳፰ በረፉም ፡ ጊዜ ፡ ተመልሰው ፡ በፊትህ ፡ ክፉ ፡ አደረጉ ፤ በጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡ ተውሃቸው ፥ ገዙአቸውም ፤ ተመልሰውም ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ በጮኹ ፡ ጊዜ ፡ ከሰማይ ፡ ሰማሃቸው ፥ እንደ ፡ ምሕረትህም ፡ ብዛት ፡ ታደግሃቸው ፤ ፳፱ ወደ ፡ ሕግህም ፡ ትመልሳቸው ፡ ዘንድ ፡ አስመሰከርህባቸው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ታበዩ ፥ ትእዛዝህንም ፡ አልሰሙም ፥ ሰውም ፡ ባደረገው ፡ ጊዜ ፡ በሕይወት ፡ የሚኖርበትን ፡ ፍርድህን ፡ ተላለፉ ፤ ትከሻቸውንም ፡ ሰጡ ፥ አንገታቸውን ፡ አደነደኑ ፥ አልሰሙምም ። ፴ ነገር ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ዓመታት ፡ ታገሥሃቸው ፥ በነቢያትህም ፡ እጅ ፡ በመንፈስህ ፡ መሰከርህባቸው ፤ አላደመጡም ፥ ስለዚህም ፡ በምድር ፡ አሕዛብ ፡ እጅ ፡ አሳልፈህ ፡ ሰጠሃቸው ። ፴፩ ነገር ፡ ግን ፡ አንተ ፡ ቸርና ፡ መሐሪ ፡ አምላክ ፡ ነህና ፡ በምሕረትህ ፡ ብዛት ፡ ፈጽመህ ፡ አላጠፋሃቸውም ፥ አልተውሃቸውምም ።

፴፪ አሁንም ፡ አምላካችን ፡ ሆይ ፥ ቃል ፡ ኪዳንንና ፡ ምሕረትን ፡ የምትጠብቅ ፡ ታላቅና ፡ ኃያል ፡ የተፈራኸውም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ ከአሦር ፡ ነገሥታት ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በእኛና ፡ በነገሥታቶቻችን ፡ በአለቆቻችንም ፡ በካህናቶቻችንም ፡ በነቢያቶቻችንም ፡ በአባቶቻችንም ፡ በሕዝብህ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የደረሰው ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ በፊትህ ፡ ጥቂት ፡ መስሎ ፡ አይታይህ ። ፴፫ በደረሰብንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ጻድቅ ፡ ነህ ፥ አንተ ፡ እውነት ፡ አድርገሃልና ፥ እኛም ፡ ኃጢአት ፡ አድርገናል ። ፴፬ ነገሥታቶቻችንም ፡ አለቆቻችንም ፡ ካህናቶቻችንም ፡ አባቶቻችንም ፡ ሕግህን ፡ አልጠበቁም ፥ የመሰከርህባቸውንም ፡ ትእዛዝህንና ፡ ምስክርህን ፡ አልሰሙህም ። ፴፭ በመንግሥታቸውም ፡ በሰጠሃቸውም ፡ ታላቅ ፡ በጎነትህ ፥ በፊታቸውም ፡ በሰጠኸው ፡ በሰባው ፡ ምድር ፡ አላመለኩህም ፥ ከክፉም ፡ ሥራቸው ፡ አልተመለሱም ። ፴፮ እነሆ ፥ ዛሬ ፡ ባሪያዎች ፡ ነን ፤ ፍሬዋንና ፡ በረከትዋን ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ ለአባቶቻችን ፡ በሰጠሃት ፡ ምድር ፥ እነሆ ፥ በእርስዋ ፡ ባሪያዎች ፡ ነን ፥ ፴፯ ስለ ፡ ኃጢአታችንም ፡ ለሾምህብን ፡ ነገሥታት ፡ በረከትዋን ፡ ታበዛለች ፤ ሰውነታችንንም ፡ ይገዛሉ ፥ በእንስሶቻችንም ፡ የሚወድዱትን ፡ ያደርጋሉ ፥ እኛም ፡ በጽኑ ፡ መከራ ፡ ላይ ፡ ነን ። ፴፰ ስለዚህም ፡ ሁሉ ፡ የታመነውን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አድርገን ፡ እንጽፋለን ፤ አለቆቻችንም ፡ ሌዋውያኖቻችንም ፡ ካህናቶቻችንም ፡ ያትሙበታል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ ያተሙትም ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ የሐካልያ ፡ ልጅ ፡ ሐቴርሰታ ፡ ነህምያ ፥ ሴዴቅያስ ፥ ፪ ሠራያ ፥ ዓዛርያስ ፥ ኤርምያስ ፥ ፫ ፋስኮር ፥ አማርያ ፥ መልክያ ፥ ፬ ሐጡስ ፥ ሰበንያ ፥ መሉክ ፥ ፭ ካሪም ፥ ሜሬሞት ፥ አብድዩ ፥ ፮ ዳንኤል ፥ ጌንቶን ፥ ባሮክ ፥ ፯ ሜሱላም ፥ አብያ ፥ ሚያሚን ፥ ፰ መዓዝያ ፥ ቤልጋይ ፥ ሸማያ ፤ እነዚህ ፡ ካህናት ፡ ነበሩ ።

፱ ሌዋውያኑም ፤ የአዛንያ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፥ ከኤንሐዳድ ፡ ልጆች ፡ ቢንዊ ፥ ቀድምኤል ፤ ፲ ወንድሞቻቸውም ፡ ሰበንያ ፥ ሆዲያ ፥ ቆሊጣስ ፥ ፈልያ ፥ ሐናን ፥ ፲፩ ሚካ ፥ ረአብ ፥ ሐሸብያ ፥ ፲፪ ዘኩር ፥ ሰራብያ ፥ ሰበንያ ፥ ፲፫ ሆዲያ ፥ ባኒ ፥ ብኒኑ ።

፲፬ የሕዝቡ ፡ አለቆች ፤ ፋሮስ ፥ ፈሐት ፡ ሞዓብ ፥ ኤላም ፥ ዛቱዕ ፥ ባኒ ፥ ፲፭ ቡኒ ፥ ዓዝጋድ ፥ ቤባይ ፥ ፲፮ አዶንያስ ፥ በጉዋይ ፥ ዓዲን ፥ ፲፯ አጤር ፥ ሕዝቅያስ ፥ ዓዙር ፥ ፲፰ ሆዲያ ፥ ሐሱም ፥ ቤሳይ ፥ ፲፱ ሐሪፍ ፥ ዓናቶት ፥ ኖባይ ፥ ፳ መግጲዓስ ፥ ሜሱላም ፥ ኤዚር ፥ ፳፩ ሜሴዜቤል ፥ ሳዶቅ ፥ ያዱአ ፥ ፳፪ ፈላጥያ ፥ ሐናን ፥ ዓናያ ፥ ፳፫ ሆሴዕ ፥ ሐናንያ ፥ አሱብ ፥ ፳፬ አሎኤስ ፥ ፈልሃ ፥ ሶቤቅ ፥ ፳፭ ሬሁም ፥ ሐሰብና ፥ መዕሤያ ፥ ፳፮ አኪያ ፥ ሐናን ፥ ዓናን ፥ ፳፯ መሉክ ፥ ካሪም ፥ በዓና ።

፳፰ የቀሩትም ፡ ሕዝብ ፥ ካህናቱም ፥ ሌዋውያኑም ፥ በረኞቹም ፥ መዘምራንም ፥ ናታኒምም ፥ ከምድርም ፡ አሕዛብ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ራሳቸውን ፡ የለዩ ፡ ሁሉ ፥ ሚስቶቻቸውም ፥ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውም ፥ የሚያውቁትና ፡ የሚያስተውሉትም ፡ ሁሉ ፡ ፳፱ ወደ ፡ ወንድሞቻቸው ፡ ወደ ፡ ታላላቆቻቸው ፡ ተጠጉ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ባሪያ ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ በተሰጠው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፥ የጌታችንንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ፍርዱንም ፡ ሥርዓቱንም ፡ ይጠብቁና ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ እርግማንና ፡ መሐላውን ፡ አደረጉ ። ፴ ሴቶች ፡ ልጆቻችንንም ፡ ለምድር ፡ አሕዛብ ፡ እንሰጥም ፥ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውንም ፡ ለልጆቻችን ፡ አንወስድም ፤ ፴፩ የምድርን ፡ አሕዛብ ፡ ሸቀጥና ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ እህል ፡ ሊገበዩ ፡ በሰንበት ፡ ቀን ፡ ቢያመጡ ፥ በሰንበት ፡ ወይም ፡ በተቀደሰው ፡ ቀን ፡ ከእነርሱ ፡ አንገዛም ፤ የሰባተኛውንም ፡ ዓመት ፡ ፍሬና ፡ ዕዳን ፡ ማስከፈል ፡ እንተዋለን ፡ ብለው ፡ ማሉ ።

፴፪ ፴፫ ስለ ፡ አምላካችንም ፡ ቤት ፡ አገልግሎት ፥ ስለ ፡ ገጸ ፡ ኅብስትም ፥ ዘወትርም ፡ በሰንበትና ፡ በመባቻ ፡ ስለ ፡ ማቅረብ ፡ ስለ ፡ እህሉ ፡ ቍርባንና ፡ ስለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፥ ስለ ፡ በዓላትም ፥ ስለ ፡ ተቀደሱትም ፡ ነገሮች ፥ ለእስራኤልም ፡ ስለሚያስተሰርየው ፡ ስለ ፡ ኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፥ ስለ ፡ አምላካችንም ፡ ቤት ፡ ሥራ ፡

ሁሉ ፡ በየዓመቱ ፡ የሰቅል ፡ ሢሶ ፡ እናመጣ ፡
ዘንድ ፡ ትእዛዝ ፡ በራሳችን ፡ ላይ ፡ አደረግን ።
፴፬ እኛም ፥ ከህናቱና ፡ ሌዋውያኑ ፡ ሕዝቡም ፥
እንደ ፡ አበቶቻችን ፡ ቤቶች ፡ በተወሰነ ፡ ጊዜ ፡
በየዓመቱ ፡ ወደ ፡ አምላካችን ፡ ቤት ፡ አምጥ
ተን ፡ በሕጉ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ በአምላካችን ፡
በእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ ይቃጠል ፡
ዘንድ ፡ ስለ ፡ እንጨት ፡ ቍርባን ፡ ዕጣ ፡ ተጣጣ
፴፭ ልን ፤ በየዓመቱም ፡ የመሬታችንን ፡ በኵራት ፥
የሁሉ ፡ ዓይነት ፡ ዛፍ ፡ የፍሬ ፡ ሁሉ ፡ በኵራት ፡
ሁሉ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እናመጣ ፡
፴፮ ዘንድ ፥ በሕጉም ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ የልጆቻች
ንንና ፡ የእንስሶቻችንን ፡ በኵራት ፥ የበሬዎ
ቻችንንና ፡ የበጎቻችንን ፡ በኵራት ፡ በአምላካ
ችን ፡ ቤት ፡ ወደሚያገለግሉት ፡ ከህናት ፡ ወደ ፡
፴፯ አምላካችን ፡ ቤት ፡ እናመጣ ፡ ዘንድ ፥ የእህላ
ችንንም ፡ በኵራት ፥ የእጅ ፡ ማንሣታችንን ፡
ቍርባን ፥ የዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ፍሬ ፥ ወይኑንና ፡ ዘይ
ቱንም ፡ ወደ ፡ ከህናቱ ፡ ወደ ፡ አምላካችን ፡
ቤት ፡ ጓዳዎች ፡ እናመጣ ፡ ዘንድ ፥ ሌዋውያ
ኑም ፡ ከከተሞቻችን ፡ እርሻ ፡ ሁሉ ፡ አሥራት ፡
ይቀበላሉና ፡ የመሬታችንን ፡ አሥራት ፡ ወደ ፡
፴፰ ሌዋውያን ፡ እናመጣ ፡ ዘንድ ፡ ማልን ። ሌዋው
ያኑም ፡ አሥራቱን ፡ በተቀበሉ ፡ ጊዜ ፡ የአሮን ፡
ልጅ ፡ ካህኑ ፡ ከሌዋውያን ፡ ጋር ፡ ይሁን ፤ ሌዋ
ውያኑም ፡ የአሥራቱን ፡ አሥራት ፡ ወደ ፡ አም
ላካችን ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ጓዳዎች ፡ ወደ ፡ ዕቃ ፡
፴፱ ቤት ፡ ያምጡት ። የእስራኤል ፡ ልጆችና ፡ የሌዊ ፡
ልጆችም ፡ የእህሉንና ፡ የወይኑን ፡ የዘይቱንም ፡
የማንሣትን ፡ ቍርባን ፡ የመቅደሱ ፡ ዕቃዎችና ፡
የሚያገለግሉት ፡ ካህናት ፡ በረኞቹና ፡ መዘም
ራኑ ፡ ወዳሉበቸው ፡ ጓዳዎች ፡ ያግቡት ፤ እንዲ
ሁም ፡ የአምላካችንን ፡ ቤት ፡ ከቶ ፡ አንተውም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ የሕዝቡም ፡ አለቆች ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተቀ
መጡ ፤ ከቀሩትም ፡ ሕዝብ ፡ ከአሥሩ ፡ ክፍል ፡
አንዱ ፡ በቅድስቲቱ ፡ ከተማ ፡ በኢየሩሳሌም ፥
ዘጠኙም ፡ በሌሎች ፡ ከተሞች ፡ ይቀመጡ ፡
፪ ዘንድ ፡ ዕጣ ፡ ተጣጣሉ ። ሕዝቡም ፡ በፈቃዳ
ቸው ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለመቀመጥ ፡ የወደዱ
ትን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ባረኩ ።

፫ በኢየሩሳሌምም ፡ የተቀመጡት ፡ የአገሩ ፡ አለ
ቆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ እስራኤል ፡ ግን ፡ ካህ
ናቱም ፡ ሌዋውያኑም ፡ ናታኒምም ፡ የሰሎሞ
ንም ፡ ባሪያዎች ፡ ልጆች ፡ እያንዳንዳቸው ፡ በየ
ርስታቸውና ፡ በየከተማቸው ፡ በይሁዳ ፡ ከተ
፬ ሞች ፡ ተቀመጡ ። ከይሁዳና ፡ ከብንያምም ፡
ልጆች ፡ እነዚህ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተቀመጡ ።
ከይሁዳ ፡ ልጆች ፤ ከፋሬስ ፡ ልጆች ፡ የመላል
ኤል ፡ ልጅ ፡ የሰፋጥያስ ፡ ልጅ ፡ የአማርያ ፡ ልጅ ፡
፭ የዘካርያስ ፡ ልጅ ፡ የዖዝያ ፡ ልጅ ፡ አታያ ፤ የሴ
ሎናዊውም ፡ ልጅ ፡ የዘካርያስ ፡ ልጅ ፡ የዮያ
ሪብ ፡ ልጅ ፡ የዓዳያ ፡ ልጅ ፡ የዖዛያ ፡ ልጅ ፡ የከ
ልሖዜ ፡ ልጅ ፡ የበሮክ ፡ ልጅ ፡ መዕሤያ ። በኢ
፮ የሩሳሌም ፡ የተቀመጡት ፡ የፋሬስ ፡ ልጆች ፡
ሁሉ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ ስምንት ፡ ጽኑዓን ፡
ነበሩ ።

፯ የብንያምም ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፤ የየ
ሻያ ፡ ልጅ ፡ የኢቲኤል ፡ ልጅ ፡ የመዕሤያ ፡ ልጅ ፡
የቆላያ ፡ ልጅ ፡ የፈዳያ ፡ ልጅ ፡ የዮእድ ፡ ልጅ ፡
፰ የሚሱላም ፡ ልጅ ፡ ሰሉ ። ከእርሱም ፡ በኋላ ፡
ጌቤና ፡ ሳላይ ፡ ዘጠኝ ፡ መቶም ፡ ሀያ ፡ ስምንት ።
፱ አለቃቸውም ፡ የዝክሪ ፡ ልጅ ፡ ኢዮኤል ፡ ነበረ ፤
የሐስኑአም ፡ ልጅ ፡ ይሁዳ ፡ በከተማው ፡ ላይ ፡
ሁለተኛ ፡ ነበረ ።

፲ ከካህናቱ ፤ የዮያሪብ ፡ ልጅ ፡ ዮዳኤ ፥ ያኪን ፥
፲፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ የአኪጡብ ፡
ልጅ ፡ የመራዮት ፡ ልጅ ፡ የሳዶቅ ፡ ልጅ ፡ የሚሱ
፲፪ ላም ፡ ልጅ ፡ የኪልቅያስ ፡ ልጅ ፡ ሠራያ ፥ የቤቱ
ንም ፡ ሥራ ፡ የሠሩ ፡ ወንድሞቻቸው ፡ ስምንት ፡
መቶ ፡ ሀያ ፡ ሁለት ፤ የመልክያ ፡ ልጅ ፡ የፋስኮር ፡
ልጅ ፡ የዘካርያስ ፡ ልጅ ፡ የአማሲ ፡ ልጅ ፡ የፈላልያ ፡
፲፫ ልጅ ፡ የይሮሐም ፡ ልጅ ፡ ዓዳያ ፥ ወንድሞቹም ፡
የአባቶቹ ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡
ሁለት ፤ የኢሜር ፡ ልጅ ፡ የምሺሌሞት ፡ ልጅ ፡
የአሕዛይ ፡ ልጅ ፡ የኤዝርኤል ፡ ልጅ ፡ አማስያ ፥
፲፬ ወንድሞቻቸውም ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ስምንት ፡ ጽኑ
ዓን ፡ ኃያላን ፤ አለቃቸውም ፡ የሐግዶሊም ፡
ልጅ ፡ ዘብድኤል ፡ ነበረ ።

፲፭ ከሌዋውያንም ፤ የቡኒ ፡ ልጅ ፡ የአሳብያ ፡ ልጅ ፡
የዓዝሪቃም ፡ ልጅ ፡ የአሱብ ፡ ልጅ ፡ ሻማያ ፤
፲፮ ከእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ በሜዳ ፡ በነበረው ፡
ሥራ ፡ ላይ ፡ የነበሩ ፡ የሌዋውያን ፡ አለቆች ፡ ሳበ
፲፯ ታይና ፡ ዮዛባት ፤ በጸሎትም ፡ ጊዜ ፡ ምስጋናን ፡
የሚቀንቅኑ ፡ አለቃው ፡ የአሳፍ ፡ ልጅ ፡ የዘብዲ ፡
ልጅ ፡ የሚካ ፡ ልጅ ፡ መታንያ ፥ በወንድሞቹም ፡
መከከል ፡ ሁለተኛ ፡ የነበረ ፡ በቅበቃር ፥ የኤዶ
ታምም ፡ ልጅ ፡ የጋላል ፡ ልጅ ፡ የሳሙስ ፡ ልጅ ፡
፲፰ አብድያ ። በቅድስቲቱ ፡ ከተማ ፡ የነበሩ ፡ ሌዋ
ውያን ፡ ሁሉ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ አራት ፡
ነበሩ ።

፲፱ በሮቹንም ፡ የሚጠብቁ ፡ በረኞቹ ፥ ዓቁብና ፡
ጤልሞን ፡ ወንድሞቻቸውም ፥ መቶ ፡ ሰባ ፡
፳ ሁለት ፡ ነበሩ ። ከእስራኤልም ፡ የቀሩት ፡ ከካ
ህናትና ፡ ከሌዋውያንም ፡ እያንዳንዳቸው ፡ በየ
ርስታቸው ፡ በይሁዳ ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ውስጥ ፡
፳፩ ነበሩ ። ናታኒምም ፡ በዖፌል ፡ ተቀምጠው ፡
ነበር ፤ ሲሐና ፡ ጊሽጳ ፡ በናታኒም ፡ ላይ ፡ ነበሩ ።
፳፪ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ ከነበሩ ፡
መዘምራን ፡ ከአሳፍ ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ የሚካ ፡
ልጅ ፡ የመታንያ ፡ ልጅ ፡ የሐሸብያ ፡ ልጅ ፡ የባኒ ፡
ልጅ ፡ ኦዚ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሌዋውያን ፡ አለቃ ፡
፳፫ ነበረ ። ስለ ፡ እነርሱም ፡ የንጉሥ ፡ ትእዛዝ ፡
ነበረ ፤ የመዘምራኑም ፡ ሥርዓት ፡ ለየዕለቱ ፡
፳፬ የተሠራ ፡ ነበረ ። ከይሁዳም ፡ ልጅ ፡ ከዛራ ፡
ወገን ፡ የሚሴዜቤል ፡ ልጅ ፡ ፈታያ ፡ ስለ ፡ ሕዝቡ ፡
ነገር ፡ ሁሉ ፡ በንጉሡ ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ።

፳፭ ስለ ፡ መንደሮቹና ፡ ስለ ፡ እርሾቻቸው ፤ ከይሁዳ ፡ ልጆች ፡ አያሌዎች ፡ በቂርያትአርበቅና ፡ በመንደሮችዋ ፥ በዲቦንና ፡ በመንደሮችዋም ፥ በይቀብጽኤልና ፡ በመንደሮችዋም ፥ ፳፮ ፳፯ በኢያሱ ፥ በሞላዳ ፥ በቤትጳሌጥ ፥ በሐጸርሹ ፳፰ ዓል ፥ በቤርሳብህና ፡ በመንደሮችዋ ፥ በጺቅ ፳፱ ላግ ፥ በምኮናና ፡ በመንደሮችዋ ፥ በዓይንሪ ፴ ሞን ፥ በጾርዓ ፥ በየርሙት ፥ በዛኖዋ ፡ በዓዶላም ፡ በመንደሮቻቸውም ፥ በለኪሶና ፡ በእርሻዎችዋ ፥ በዓዜቃና ፡ በመንደሮችዋ ፡ ተቀመጡ ። እንዲሁ ፡ ከቤርሳቤህ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ፴፩ ሄኖም ፡ ሸለቆ ፡ ድረስ ፡ ሰፈሩ ። የብንያምም ፡ ልጆች ፡ ከጌባ ፡ ጀምሮ ፡ በማክማስ ፥ በጋያ ፥ ፴፪ በቤቴልና ፡ በመንደሮችዋ ፥ በዓናቶት ፥ በኖብ ፥ ፴፫ ፴፬ በሐናንያ ፥ በሐጾር ፥ በራማ ፥ በጊቴም ፥ በሐ ፴፭ ዲድ ፥ በስቦይም ፥ በንበላት ፥ በሎድ ፥ በኦኖ ፥ ፴፮ በጌሐራሺም ፡ ተቀመጡ ። በይሁዳም ፡ ከነበሩ ፡ ሌዋውያን ፡ አያሌ ፡ ክፍሎች ፡ ወደ ፡ ብንያም ፡ ሆኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ ከሰላትያል ፡ ልጅ ፡ ከዘሩባቤልና ፡ ከኢያሱ ፡ ጋር ፡ የወጡት ፡ ካህናትና ፡ ሌዋውያን ፡ እነዚህ ፡ ፪ ነበሩ ፤ ሠራያ ፥ ኤርምያስ ፥ ዕዝራ ፥ አማርያ ፥ ፫ መሉክ ፥ ሐጡስ ፥ ሴኬንያ ፥ ሬሁም ፥ ሚሬ ፬ ፭ ሞት ፥ አዶ ፥ ጌንቶን ፥ አብያ ፥ ሚያሚን ፥ ፮ መዓድያ ፥ ቢልጋ ፥ ሸማያ ፥ ዮያሪብ ፥ ዮዳኤ ፥ ፯ ሰሉ ፥ ዓሞቅ ፥ ኬልቅያስ ፥ ዮዳኤ ፤ እነዚህ ፡ በኢያሱ ፡ ዘመን ፡ የካህናቱና ፡ የወንድሞቻቸው ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ።

፰ ሌዋውያኑም ፤ ኢያሱ ፥ ቢንዊ ፥ ቀድምኤል ፥ ሰራብያ ፥ ይሁዳ ፥ ከወንድሞቹም ፡ ጋር ፡ በመ ፱ ዝሙራን ፡ ላይ ፡ የነበረ ፡ መታንያ ። ወንድሞቻቸውም ፡ በቀቡቅያና ፡ ዑኒ ፡ በየሰሞናቸው ፡ ፲ በአንጻራቸው ፡ ነበሩ ። ኢያሱም ፡ ዮአቂምን ፡ ወለደ ፥ ዮአቂምም ፡ ኤልያሴብን ፡ ወለደ ፥ ኤል ፲፩ ያሴብም ፡ ዮአዳን ፡ ወለደ ፥ ዮአዳም ፡ ዮናታንን ፡ ወለደ ፥ ዮናታንም ፡ ያዱአን ፡ ወለደ ። ፲፪ በዮአቂምም ፡ ዘመን ፡ የአባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ እነዚህ ፡ ካህናቱ ፡ ነበሩ ፤ ከሠራያ ፡ ምራያ ፥ ፲፫ ከኤርምያስ ፡ ሐናንያ ፥ ከዕዝራ ፡ ሚሱላም ፥ ፲፬ ከአማርያ ፡ ይሆሐናን ፥ ከመሉኪ ፡ ዮናታን ፥ ፲፭ ከሰበንያ ፡ ዮሴፍ ፥ ከካሬም ፡ ዓድና ፥ ከመራ ፲፮ ዮት ፡ ሔልቃይ ፥ ከአዶ ፡ ዘካርያስ ፥ ከጌንቶን ፡ ፲፯ ሚሱላም ፥ ከአብያ ፡ ዝክሪ ፥ ከሚያሚን ፡ ሞዓ ፲፰ ድያ ፥ ፈልጣይ ፥ ከቢልጋ ፡ ሳሙስ ፥ ከሸማያ ፡ ፲፱ ዮናታን ፥ ከዮያሪብ ፡ መትናይ ፥ ከዮዳኤ ፡ ፳ አዚ ፥ ከሳላይ ፡ ቃላይ ፥ ከዓሞቅ ፡ ዔቤር ፥ ፳፩ ከኬልቅያስ ፡ ሐሸብያ ፥ ከዮዳኤ ፡ ናትናኤል ።

፳፪ ከሌዋውያኑም ፡ በኤልያሴብና ፡ በዮአዳ ፥ በዮሐናንና ፡ በያዱአ ፡ ዘመን ፡ የአባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ ተጻፉ ፤ ካህናቱም ፡ በፋርሳዊው ፡ በዳ ፳፫ ርዮስ ፡ መንግሥት ፡ ዘመን ፡ ተጻፉ ። የሌዊ ፡ ልጆች ፡ የአባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቆች ፡ እስከ ፡ ኤልያሴብ ፡ ልጅ ፡ እስከ ፡ ዮሐናን ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ በታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ተጻፉ ። ፳፬ የሌዋውያኑም ፡ አለቆች ፤ ሐሸብያ ፥ ሰራብያ ፥ የቀድምኤልም ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፡ ትእዛዝ ፡ በየሰሞናቸው ፡ በወንድሞቻቸው ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ያከብሩና ፡ ያመሰግኑ ፡ ነበር ። ፳፭ መታንያ ፥ በቀቡቅያ ፥ አብድዩ ፥ ሚሱላም ፥ ጤልሞን ፥ ዓቁብ ፡ በበሮች ፡ አጠገብ ፡ የሚገኙትን ፡ ዕቃ ፡ ቤቶች ፡ ለመጠበቅ ፡ በረኞች ፡ ነበሩ ። ፳፮ እነዚህ ፡ በኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ በኢያሱ ፡ ልጅ ፡ በዮአቂም ፡ በአለቃው ፡ በነህምያ ፡ በጸሐፊውም ፡ በካህኑ ፡ በዕዝራ ፡ ዘመን ፡ ነበሩ ።

፳፯ የኢየሩሳሌምንም ፡ ቅጥር ፡ በቀደሱ ፡ ጊዜ ፡ ቅዳሴውን ፡ በደስታና ፡ በምስጋና ፡ በመዝሙርም ፡ በጸናጽልም ፡ በበገናም ፡ በመሰንቆም ፡ ለማድረግ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ያመጡአቸው ፡ ዘንድ ፡ ሌዋውያኑን ፡ በየስፍራቸው ፡ ሁሉ ፡ ፈለጉ ። ፳፰ ፳፱ መዘምራኑም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ዙሪያ ፡ መንደሮች ፡ ሠርተው ፡ ነበርና ፡ የመዘምራኑ ፡ ልጆች ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ዙሪያና ፡ ከነጦፋውያን ፡ መንደሮች ፥ ከቤትጌልገላም ፥ ከጌባና ፡ ከዓዝሞት ፡ እርሻዎች ፡ ተሰበሰቡ ። ፴ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑም ፡ ራሳቸውን ፡ አነጹ ፤ ሕዝቡንም ፡ በሮቹንም ፡ ቅጥሩንም ፡ አነጹ ።

፴፩ የይሁዳንም ፡ አለቆች ፡ ወደ ፡ ቅጥሩ ፡ ላይ ፡ አወጣኋቸው ፤ አመስጋኞቹንም ፡ በሁለት ፡ ታላላቅ ፡ ተርታ ፡ አቆምኋቸው ፤ አንዱም ፡ ወደ ፡ ቀኝ ፡ በቅጥሩ ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ጕድፍ ፡ መጣያው ፡ በር ፡ ሄደ ። ፴፪ ከእነርሱም ፡ በኋላ ፡ ሆሻያ ፥ የይሁዳም ፡ አለቆች ፡ እኩሌታ ፥ ፴፫ ዓዛርያስ ፥ ዕዝራ ፥ ሚሱላም ፥ ፴፬ ይሁዳ ፥ ብንያም ፥ ሸማያ ፥ ኤርምያስ ፥ ፴፭ መለከትም ፡ ይዘው ፡ ከካህናቱ ፡ ልጆች ፡ አያሌዎች ፥ የአሳፍም ፡ ልጅ ፡ የዘኩር ፡ ልጅ ፡ የሚካያ ፡ ልጅ ፡ የመታንያ ፡ ልጅ ፡ የሸማያ ፡ ልጅ ፡ የዮናታን ፡ ልጅ ፡ ዘካርያስ ፥ ፴፮ ወንድሞቹም ፡ ሸማያ ፥ ኤዝርኤል ፥ ሚላላይ ፥ ጊላላይ ፥ መዓይ ፥ ናትናኤል ፥ ይሁዳ ፥ አናኒ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሰው ፡ የዳዊትን ፡ የዜማውን ፡ ዕቃ ፡ ይዘው ፡ ሄዱ ፤ ጸሐፊውም ፡ ዕዝራ ፡ በፊታቸው ፡ ነበረ ። ፴፯ በምንጭም ፡ በር ፡ አቅንተው ፡ ሄዱ ፤ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ደረጃ ፥ በቅጥሩም ፡ መውጫ ፥ ከዳዊትም ፡ ቤት ፡ በላይ ፡ እስከ ፡ ውኃው ፡ በር ፡ ድረስ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ሄዱ ።

፴፰ ሁለተኛውም ፡ የአመስጋኞቹ ፡ ተርታ ፡ ወደ ፡ ግራ ፡ ሄደ ፤ እኔና ፡ የሕዝቡም ፡ እኩሌታ ፡ በስተኋላቸው ፡ ነበርን ፤ በቅጥሩም ፡ ላይ ፥ በእቶኑ ፡ ግንብ ፡ በላይ ፡ እስከ ፡ ሰፊው ፡ ቅጥር ፡ ድረስ ፥ ፴፱ ከኤፍሬምም ፡ በር ፡ በላይ ፥ በአሮጌው ፡ በርና ፡ በዓሣ ፡ በር ፡ በሐናንኤልም ፡ ግንብ ፥ በሃሜአ ፡ ግንብ ፡ እስከ ፡ በጎች ፡ በር ፡ ድረስ ፡ ሄዱ ፤ በዘበኞችም ፡ በር ፡ አጠገብ ፡ ቆሙ ። ፵ እንዲሁ ፡ ሁለቱ ፡ የአመስጋኞች ፡ ተርታዎች ፡ በእግዚአ

ብሔር ፡ ቤት ፡ ቆሙ ፤ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ እኔና ፡
፵፩ የአለቆች ፡ እኩሌታ ÷ ካህናቱም ፡ ኤልያቄም ÷
መዕሤያ ÷ ሚንያሚን ÷ ሚክያ ÷ ኤልዮዔናይ ÷
፵፪ ዘካርያስ ÷ ሐናንያ ፡ መለከት ፡ ይዘው ÷ መዕ
ሤያ ÷ ሸማያ ÷ አልዓዛር ÷ ኦዚ ÷ ይሆሐናን ÷
መልክያ ÷ ኤላም ÷ ኤጽር ፡ ቆምን ። መዘምራ
ኑም ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ዘመሩ ÷ አለቃቸውም ፡
፵፫ ይዝረሕያ ፡ ነበረ ። እግዚአብሔርም ፡ በታላቅ ፡
ደስታ ፡ ደስ ፡ አሰኝቶአቸዋልና ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡
ትልቅ ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረቡ ÷ ደስም ፡ አላ
ቸው ፤ ሴቶቹና ፡ ልጆቹም ፡ ደግሞ ፡ ደስ ፡ አላ
ቸው ፤ የኢየሩሳሌምም ፡ ደስታ ፡ ከሩቅ ፡ ተሰማ ።

፵፬ ይሁዳም ፡ በአገልጋዮቹ ፡ ካህናትና ፡ ሌዋ
ውያን ፡ ደስ ፡ ስላላቸው ÷ የካህናቱንና ፡ የሌ
ዋውያኑን ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ ከከ
ተሞች ፡ እርሻዎች ፡ ያከማቹ ፡ ዘንድ ፡ ለእጅ ፡
ማንሣት ፡ ቍርባንና ፡ ለበኵራት ፡ ለአሥራ
ትም ፡ በየዕቃ ፡ ቤቶቹ ፡ ላይ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡
፵፭ ሰዎች ፡ ተሾሙ ። እነርሱም ፡ መዘምራኑና ፡
በረኞቹም ፡ የአምላካቸውን ፡ ሥርዓት ፡ የመን
ጻታቸውንም ፡ ሥርዓት ፡ እንደ ፡ ዳዊትና ፡
እንደ ፡ ልጁ ፡ እንደ ፡ ሰሎሞን ፡ ትእዛዝ ፡ ጠበቁ ።
፵፮ አስቀድሞም ፡ በዳዊትና ፡ በአሳፍ ፡ ዘመን ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ በዜማ ፡ ለማመስገንና ፡ ለማክበር ፡
፵፯ የመዘምራን ፡ አለቆች ፡ ነበሩ ። እስራኤልም ፡
ሁሉ ፡ በዘሩባቤልና ፡ በነህምያ ፡ ዘመን ፡ ለመ
ዘምራኑና ፡ ለበረኞቹ ፡ እድል ፡ ፈንታቸውን ፡
በየዕለቱ ፡ ይሰጡ ፡ ነበር ፤ የተቀደሰውንም ፡
ነገር ፡ ለሌዋውያን ፡ ሰጡ ÷ ሌዋውያኑም ፡ ከተ
ቀደሰው ፡ ነገር ፡ ለአሮን ፡ ልጆች ፡ ሰጡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ በዚያም ፡ ቀን ፡ የሙሴን ፡ መጽሐፍ ፡ በሕ
ዝቡ ፡ ጆሮ ፡ አነበቡ ፤ አሞናውያንና ፡ ሞዓብ
ውያንም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጉባኤ ፡ ለዘላ
፪ ለም ፡ እንዳይገቡ ፡ የሚል ፡ በዚያ ፡ ተገኘ ። የእ
ስራኤልን ፡ ልጆች ፡ በእንጀራና ፡ በውኃ ፡ ስላ
ልተቀበሉአቸውና ፡ ይረግማቸው ፡ ዘንድ ፡ በለ
ዓምን ፡ ስለ ፡ ገዙባቸው ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡
አምላካችን ፡ እርግማኑን ፡ ወደ ፡ በረከት ፡ መለ
፫ ሰው ። ሕጉንም ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ድብልቁን ፡
ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ከእስራኤል ፡ ለዩ ።

፬ ከዚህም ፡ አስቀድሞ ፡ በአምላካችን ፡ ቤት ፡
ጓዳዎች ፡ ላይ ፡ ተሾሞ ፡ የነበረው ፡ ካህኑ ፡ ኤል
፭ ያሴብ ፡ ከጦቢያ ፡ ጋር ፡ ተወዳጅቶ ÷ ለሌዋው
ያን ÷ ለመዘምራን ÷ ለበረኞቹ ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡
የተሰጣቸውን ፡ የእህሉን ፡ ቍርባንና ፡ ዕጣኑን ÷
ዕቃዎቹንም ÷ የእህሉንና ፡ የወይኑን ፡ የዘይቱ
ንም ፡ አሥራት ÷ ለካህናቱም ፡ የሆነውን ፡ የማ
ንሣት ፡ ቍርባን ፡ አስቀድሞ ፡ ያስቀመጡበትን ፡
፮ ታላቁን ፡ ጓዳ ፡ አዘጋጅቶለት ፡ ነበር ። እኔ ፡ ግን ፡
በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ በአርጤክስስ ፡ በሠላሳ ፡
ሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ሄጄ ፡ ነበ
ርና ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አልነበር

ሁም ። ከጥቂት ፡ ዘመንም ፡ በኋላ ፡ የንጉሡን ፡
፯ ፈቃድ ፡ ለመንሁ ፤ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡
መጣሁ ፤ ኤልያሴብም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
አደባባይ ፡ ለጦብያ ፡ ጓዳውን ፡ በማዘጋጀት ፡
፰ ያደረገውን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አስተዋልሁ ። እጅ
ግም ፡ አስከፋኝ ፤ የጦብያንም ፡ የቤቱን ፡ ዕቃ ፡
፱ ሁሉ ፡ ከጓዳ ፡ ወደ ፡ ውጪ ፡ ጣልሁ ። ጓዳዎቹ
ንም ፡ እንዲያነጹ ፡ አዘዝሁ ፤ የእግዚአብሔር
ንም ፡ ቤት ፡ ዕቃዎች ፡ የእህሉንም ፡ ቍርባን ፡
ዕጣኑንም ፡ መልሼ ፡ በዚያ ፡ አገባሁ ።

፲ ለሌዋውያንም ፡ እድል ፡ ፈንታቸው ፡ እንዳ
ልተሰጠ ÷ የሚያገለግሉትም ፡ ሌዋውያንና ፡
መዘምራን ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ እርሻው ፡ እንደ ፡
፲፩ ሄዱ ፡ ተመለከትሁ ። እኔም ፡— የእግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ተተወ ? ብዬ ፡ ከአለቆቹ ፡
ጋር ፡ ተከራከርሁ ። ሰበሰብኋቸውም ÷ በየስፍ
፲፪ ራቸውም ፡ አቆምኋቸው ። ይሁዳም ፡ ሁሉ ፡
የእህሉንና ፡ የወይኑን ፡ የዘይቱንም ፡ አሥራት ፡
፲፫ ወደ ፡ ዕቃ ፡ ቤቶች ፡ አመጡ ። በዕቃ ፡ ቤቶችም ፡
ላይ ፡ ካህኑን ፡ ሰሌምያን ÷ ጸሐፊውንም ፡ ሳዶ
ቅን ÷ ከሌዋውያኑም ፡ ፈዳያን ፡ ሾምሁ ፤ ከእነ
ርሱም ፡ ጋር ፡ የመታንያ ፡ ልጅ ፡ የዘኩር ፡ ልጅ ፡
ሐናን ፡ ነበረ ፤ እነርሱም ፡ የታመኑ ፡ ሆነው ፡
ተገኙ ÷ ሥራቸውም ፡ ለወንድሞቻቸው ፡ ማከ
፲፬ ፋፈል ፡ ነበረ ። አምላኬ ፡ ሆይ ÷ ስለዚህ ፡ አስ
በኝ ፤ ለአምላኬም ፡ ቤት ፡ ያደረግሁትን ፡ ወረ
ታዬን ፡ አታጥፋ ።

፲፭ በዚያም ፡ ወራት ፡ በይሁዳ ፡ በሰንበት ፡ ቀን ፡
የወይን ፡ መጥመቂያን ፡ የሚረግጡትን ÷ ነዶም ፡
የሚከመሩትን ÷ የወይኑን ፡ ጠጅና ፡ የወይኑን ፡
ዘለላ ፡ በለሱንም ፡ ልዩ ፡ ልዩም ፡ ዓይነት ፡ ሸክም ፡
በአህዮች ፡ ላይ ፡ የሚጭኑትን ÷ በሰንበትም ፡
ቀን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ የሚያስገቡትን ፡
አየሁ ፤ ገበያ ፡ በደረጉበትም ፡ ቀን ፡ አስመሰክ
፲፮ ርሁባቸው ። ደግሞም ፡ በእርስዋ ፡ የተቀመጡ ፡
የጢሮስ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ እነርሱም ፡ ዓሣዎችን ፡
ልዩ ፡ ልዩም ፡ ዓይነት ፡ ሸቀጥ ፡ አምጥተው ፡
በሰንበት ፡ ቀን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለይሁዳ ፡
፲፯ ልጆች ፡ ይሸጡ ፡ ነበር ። ከይሁዳም ፡ ታላላቆች ፡
ጋር ፡ ተከራከርሁና ፡— ይህ ፡ የምታደርጉት ፡
ክፉ ፡ ነገር ፡ ምንድር ፡ ነው ? የሰንበትንስ ፡ ቀን ፡
፲፰ ታረክሳላችሁን ? አባቶቻችሁ ፡ እንደዚህ ፡ አድ
ርገው ፡ አልነበረምን ? አምላካችንስ ፡ ይህን ፡
ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በእኛና ፡ በዚህ ፡ ከተማ ፡
ላይ ፡ አምጥቶ ፡ አልነበረምን ? እናንተም ፡ ሰን
በትን ፡ በማርከሳችሁ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ መዓ
ትን ፡ ትጨምራላችሁ ፡ አልኋቸው ።

፲፱ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከሰንበት ፡ በፊት ፡ በኢየሩሳ
ሌም ፡ በሮች ፡ ድንግዝግዝታ ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡
በሮችዋ ፡ እንዲዘጉ ÷ ሰንበትም ፡ እስኪያልፍ ፡
ድረስ ፡ እንዳይከፈቱ ፡ አዘዝሁ ። በሰንበትም ፡
ቀን ፡ ሸክም ፡ እንዳይገባ ፡ ከብላቴኖቼ ፡ በአያሌ
፳ ዎቹ ፡ በሮችዋን ፡ አስጠበቅሁ ። ሁሉም ፡ አንድ ፡
ወይም ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ውጭ ፡

፳፩፤ አድረው ፡ ገበያ ፡ አድርገው ፡ ነበር ። እኔም ፡
አስመሰከርሁባቸውና ፡— በቅጥሩ ፡ ውጭ ፡
ለምን ፡ ታድራላችሁ ? እንደ ፡ ገና ፡ ብታደር
ጉት ፡ እጆቼን ፡ አነሣባችኋለሁ ፡ አልኋቸው ።
ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ በሰንበት ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ገና ፡
፳፪፤ አልመጡም ። ሌዋውያኑንም ፡ ራሳቸውን ፡ እን
ዲያነጹ ÷ መጥተውም ፡ በሮቹን ፡ እንዲጠብቁ ÷
የሰንበትንም ፡ ቀን ፡ እንዲቀድሱ ፡ ነገርኋቸው ።
አምላኬ ፡ ሆይ ÷ ስለዚህ ፡ ደግሞ ፡ አስበኝ ÷
እንደ ፡ ምሕረትህም ፡ ብዛት ፡ ራራልኝ ።

፳፫፤ ደግሞም ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ የአዛጦንና ፡ የአ
ሞንን ፡ የሞዓብንም ፡ ሴቶች ፡ ያገቡትን ፡ አይ
፳፬፤ ሁድ ፡ አየሁ ። ከልጆቻቸውም ፡ እኩሌቶቹ ፡
በአዛጦን ፡ ቋንቋ ፡ ይናገሩ ፡ ነበር ÷ በአይሁድም ፡
፳፭፤ ቋንቋ ፡ መናገር ፡ አያውቁም ፡ ነበር ። ከእነር
ሱም ፡ ጋር ፡ ተከራከርሁ ÷ ረገምኋቸውም ፤
ከእነርሱም ፡ አያሌዎቹን ፡ መታሁ ÷ ጠጉራቸ
ውንም ፡ ነጩሁ ÷ እንዲህም ፡ ብዬ ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ አማልኋቸው ፡— ሴቶች ፡ ልጆቻች
ሁን ፡ ለወንዶች ፡ ልጆቻቸው ፡ አትስጡ ÷
ሴቶች ፡ ልጆቻቸውንም ፡ ለእናንተና ፡ ለልጆቻ
ችሁ ፡ አትውሰዱ ። የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ሰሎ ፳፮፤
ሞን ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ኃጢአት ፡ አድርጎ ፡ የለ
ምን ? በብዙ ፡ አሕዛብም ፡ መካከል ፡ እንደ ፡
እርሱ ፡ ያለ ፡ ንጉሥ ፡ አልነበረም ÷ በአምላ
ኩም ፡ ዘንድ ፡ የተወደደ ፡ ነበረ ÷ እግዚአብ
ሔርም ፡ በእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አንግሦት ፡
ነበር ፤ እርሱንም ፡ እንኳ ፡ እንግዶች ፡ ሴቶች ፡
አሳቱት ። በውኑ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ታላቅ ፡ ክፋት ፡ ፳፯፤
እንሠራ ÷ እንግዶችንም ፡ ሴቶች ፡ በማግባት ፡
አምላካችን ፡ እንበድል ፡ ዘንድ ፡ እናንተን ፡ እን
ስማ ?

ከዋነኛውም ፡ ካህን ፡ ከኤልያሴብ ፡ ልጅ ፡ ከዮ ፳፰፤
አዳ ፡ ልጆች ፡ አንዱ ፡ ለሖሮናዊው ፡ ለሰንባላጥ ፡
አማች ፡ ነበረ ፤ ከእኔም ፡ ዘንድ ፡ አባረርሁት ።
አምላኬ ፡ ሆይ ÷ ክህነትን ፡ የክህነትንና ፡ የሌዋ ፳፱፤
ውያንንም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ስላፈረሱ ፡ አስባቸው ።

ከእንግዳ ፡ ነገርም ፡ ሁሉ ፡ አነጻኋቸው ፤ ለካ ፴፤
ህናቱና ፡ ለሌዋውያኑም ፡ እያንዳንዳቸው ፡ በየ
ሰሞናቸው ÷ በየጊዜውም ፡ ለእንጨት ፡ ቍር ፴፩፤
ባን ፡ ለበኵራቱም ፡ ሥርዓት ፡ አደረግሁ ። አም
ላኬ ፡ ሆይ ÷ በመልካም ፡ አስበኝ ።

# መ ጽ ሐ ፈ ፡ አ ስ ቴ ር ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ በአርጤክስስም፡ዘመን፡እንዲህ፡ሆነ፤ይህም፡
አርጤክስስ ፡ ከህንድ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኢትዮ
ጵያ ፡ ድረስ ፡ በመቶ ፡ ሀያ ፡ ሰባት ፡ አገሮች ፡
፪፤ ላይ ፡ ነገሠ ። በዚያም ፡ ዘመን ፡ ንጉሡ ፡ አርጤ
ክስስ፡በሱሳ፡ግንብ፡በነበረው፡በመንግሥቱ፡
፫፤ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፥ በነገሠ፡በሦስተ
ኛው ፡ ዓመት ፡ ለባለምዋሎቹና ፡ ለአገልጋዮቹ ፡
ሁሉ ፡ ግብዣ ፡ አደረገ ፤ የፋርስና ፡ የሜዶን ፡
ታላላቆች ፡ ሁሉ ፥ የየአገሩ ፡ አዛውንትና ፡ ሹማ
፬፤ ምት ፥ በፊቱ ፡ ነበሩ ፤ የከበረውንም ፡ የመንግ
ሥቱን ፡ ሀብት ፥ የታላቁንም ፡ የግርማዊነቱን ፡
ክብር ፡ መቶ ፡ሰማንያ ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ አሳያቸው ።
፭፤ ይህም ፡ ቀን ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡
ውስጥ ፡ ለተገኙት ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ከታላቁ ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታናሹ ፡ ድረስ ፡ ንጉሡ ፡ በን
ጉሡ ፡ ቤት ፡ አታክልት ፡ ውስጥ ፡ ባለው ፡ አደ
፮፤ በባይ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ግብዣ ፡ አደረገ ። ነጭ ፥
አረንጓዴ ፥ ሰማያዊም ፡ መጋረጆች ፡ ከጥሩ ፡
በፍታና ፡ ከሐምራዊ ፡ ግምጃ ፡ በተሠራ ፡ ገመድ ፥
በብር ፡ ቀለበትና ፡ በዕብነ ፡ በረድ ፡ አዕማድ ፡
ላይ ፡ ተዘርግተው ፡ ነበር ፤ አልጋዎቹም ፡ ከወ
ርቅና ፡ ከብር ፡ ተሠርተው ፡ በቀይና ፡ በነጭ ፡
በብጫና ፡ በጥቁር ፡ ዕብነ ፡ በረድ ፡ ወለል ፡ ላይ ፡
፯፤ ነበሩ ። መጠጡም ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ በወርቅ ፡
ዕቃ ፡ ይታደል ፡ ነበር ፤ የንጉሡም ፡ የወይን ፡
ጠጅ ፡ እንደ ፡ ንጉሡ ፡ ለጋስነት ፡ መጠን ፡ እጅግ ፡
፰፤ ብዙ ፡ ነበረ ። ንጉሡም ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡
ፈቃድ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ለቤቱ ፡ አዛዦች ፡
ሁሉ ፡ አዝዞ ፡ ነበርና ፡ መጠጡ ፡ እንደ ፡ ወግ ፡
፱፤ አልነበረም ። ንግሥቲቱም ፡ አስጢን ፡ በንጉሡ ፡
በአርጤክስስ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ለሴቶች ፡
ግብዣ ፡ አደረገች ።
፲፤፲፩፤ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ ንጉሡ ፡ አርጤክስስ ፡
የወይን ፡ ጠጅ ፡ ጠጥቶ ፡ ደስ ፡ ባለው ፡ ጊዜ ፥
ንግሥቲቱ ፡ አስጢን ፡ መልከ ፡ መልካም ፡ ነበ
ረችና ፡ ውበትዋ ፡ ለአሕዛብና ፡ ለአለቆች ፡ እን
ዲታይ ፡ የመንግሥቱን ፡ ዘውድ ፡ ጭነው ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ ፊት ፡ ያመጡአት ፡ ዘንድ ፡ በፊቱ ፡ የሚ
ያገለግሉትን ፡ ሰባቱን ፡ ጃንደረቦች ፡ ምሁማ
ንን ፥ ባዛንን ፥ ሐርቦናን ፥ ገበታን ፥ ዘቶልታን ፥
፲፪፤ ዜታርን ፥ ከርከስን ፡ አዘዛቸው ። ነገር ፡ ግን ፡
ንግሥቲቱ ፡ አስጢን ፡ በጃንደረቦቹ ፡ እጅ ፡ በላ
ከው ፡ በንጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ ትመጣ ፡ ዘንድ ፡
እንቢ ፡ አለች ፤ ንጉሡም ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ፥
በቍጣውም ፡ ተናደደ ።
፲፫፤ ሕግንና ፡ ፍርድን ፡ በሚያውቁ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡
የንጉሡ ፡ ወግ ፡ እንዲህ ፡ ነበረና ፡ ንጉሡ ፡ የዘ
መኑን ፡ ነገር ፡ የሚያውቁትን ፡ ጥበበኞችን ፥
፲፬፤ በመንግሥቱም ፡ ቀዳሚዎች ፡ ሆነው ፡ የሚቀ
መጡ ፡ የንጉሡ ፡ ባለምዋሎች ፡ ሰባቱ ፡ የፋ
ርስና ፡ የሜዶን ፡ መሳፍንት ፡ አርቄስዮስ ፥
ሼታር ፥ አድማታ ፥ ተርሺሽ ፥ ሜሬስ ፥ ማሌ
፲፭፤ ሴዓር ፥ ምሙካን ፡ በአጠገቡ ፡ ሳሉ ፡— በጃን
ደረቦች ፡ እጅ ፡ የተላከበትን ፡ የንጉሡን ፡ የአር
ጤክስስን ፡ ትእዛዝ ፡ ስላላደረገች ፡ በንግሥቲቱ ፡
በአስጢን ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ የምናደርገው ፡
ምንድር ፡ ነው ? አላቸው ።
፲፮፤ ምሙካንም ፡ በንጉሡና ፡ በአዛውንቱ ፡ ፊት ፡
እንዲህ ፡ አለ ፡— ንግሥቲቱ ፡ አስጢን ፡ አዛው
ንቱን ፡ ሁሉና ፡ በንጉሡ ፡ በአርጤክስስ ፡ አገር ፡
ያሉትን ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ በድላለች ፡ እንጂ ፡
፲፯፤ ንጉሡን ፡ ብቻ ፡ የበደለች ፡ አይደለችም ። ይህ ፡
የንግሥቲቱ ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ይደ
ርሳልና ፡— ንጉሡ ፡ አርጤክስስ ፡ ንግሥቲቱ ፡
አስጢን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ትገባ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፥
እርስዋ ፡ ግን ፡ አልገባችም ፡ ተብሎ ፡ በተነገረ ፡
ጊዜ ፡ ባሎቻቸው ፡ በዓይናቸው ፡ ዘንድ ፡ የተ
፲፰፤ ናቁ ፡ ይሆናሉ ። ዛሬም ፡ የንግሥቲቱን ፡ ነገር ፡
የሰሙት ፡ የፋርስና ፡ የሜዶን ፡ ወይዛዝር ፡ እን
ዲህና ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ ለንጉሡ ፡ አዛውንት ፡
ሁሉ ፡ ይናገራሉ ፥ ንቀትና ፡ ቍጣም ፡ ይበዛል ።
፲፱፤ ንጉሡም ፡ ቢፈቅድ ፥ አስጢን ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡
ወደ ፡ አርጤክስስ ፡ ፊት ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
እንዳትገባ ፡ የንጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ ከእርሱ ፡ ይውጣ ፥
እንዳይፈርስም ፡ በፋርስና ፡ በሜዶን ፡ ሕግ ፡
ይጻፍ ፤ ንጉሡም ፡ ንግሥትነትዋን ፡ ከእርስዋ ፡
፳፤ ለተሻለችው ፡ ለሌላይቱ ፡ ይስጥ ። የንጉሡም ፡
ትእዛዝ ፡ በሰፊው ፡ መንግሥቱ ፡ ሁሉ ፡ በተነ
ገረ ፡ ጊዜ ፡ ሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ባሎቻቸውን ፡ ታላ
፳፩፤ ቁንም ፡ ታናሹንም ፡ ያከብራሉ ። ይህም ፡
ምክር ፡ ንጉሡንና ፡ አዛውንቱን ፡ ደስ ፡ አሰኛ
ቸው ፤ ንጉሡም ፡ እንደ ፡ ምሙካን ፡ ቃል ፡ አደ
፳፪፤ ረገ ። ሰው ፡ ሁሉ ፡ በቤቱ ፡ አለቃ ፡ ይሁን ፤
በሕዝቡም ፡ ቋንቋ ፡ ይናገር ፡ ብሎ ፡ ለአገሩ ፡
ሁሉ ፡ እንደ ፡ ጽሕፈቱ ፡ ለሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡
እንደ ፡ ቋንቋው ፡ ደብዳቤዎችን ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡
አገሮች ፡ ሁሉ ፡ ሰደደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፤ ከዚህም ፡ ነገር ፡ በኋላ ፡ የንጉሡ ፡ የአርጤክ
ስስ ፡ ቍጣ ፡ በበረደ ፡ ጊዜ ፡ አስጢንና ፡ ያደረገ
፪፤ ችውን ፡ የፈረደባትንም ፡ ነገር ፡ አሰበ ። ንጉ
ሡንም ፡ የሚያገለግሉ ፡ ብላቴኖች ፡ እንዲህ ፡
አሉት ፡— መልከ ፡ መልካም ፡ የሆኑ ፡ ደናግል ፡
፫፤ ለንጉሡ ፡ ይፈለጉለት ፤ ሴቶችን ፡ ከሚጠብቅ ፡
ከንጉሡ ፡ ጃንደረባ ፡ ከሄጌ ፡ እጅ ፡ በታች ፡
እንዲያደርጓቸው ፡ መልከ ፡ መልካሞቹን ፡ ደና
ግል ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ሱሳ ፡ ግንብ ፡ ወደ ፡ ሴቶች ፡

ቤት ፡ ይሰበስቡአቸው ፡ ዘንድ ፡ ንጉሡ ፡ በመንግሥቱ ፡ አገሮች ፡ ሁሉ ፡ ሹማምቶችን ፡ ያኑር ፤ ቀበትና ፡ የሚያስፈልጋቸውም ፡ ይሰጣቸው ፤ ፬ ንጉሡንም ፡ ደስ ፡ የምታሰኝ ፡ ቆንጆ ፡ በአስጢን ፡ ስፍራ ፡ ትንገሥ ። ይህም ፡ ነገር ፡ ንጉሡን ፡ ደስ ፡ አሰኘው ፥ እንዲሁም ፡ አደረገ ።

፭ አንድ ፡ አይሁዳዊ ፡ የቂስ ፡ ልጅ ፡ የሰሚኢ ፡ ልጅ ፡ የኢያዕር ፡ ልጅ ፡ መርዶክዮስ ፡ የሚባል ፡ ፮ ብንያማዊ ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡ ነበረ ። እርሱም ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ከማረካቸው ፡ ከይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ከኢኮንያን ፡ ጋር ፡ ከተማረኩት ፡ ምርኮኞች ፡ ጋር ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ የተማ ፯ ረከ ፡ ነበረ ። አባትና ፡ እናትም ፡ አልነበራትምና ፡ የአጎቱ ፡ ልጅ ፡ ሀደሳ ፡ የተባለችውን ፡ አስቴርን ፡ አሳድጎ ፡ ነበር ፤ ቆንጆይቱም ፡ የተዋበችና ፡ መልከ ፡ መልካም ፡ ነበረች ፤ አባትዋና ፡ እናትዋም ፡ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ መርዶክዮስ ፡ እንደ ፡ ልጁ ፡ አድርጎ ፡ ወስዶአት ፡ ነበር ።

፰ የንጉሡም ፡ ትእዛዝና ፡ አዋጅ ፡ በተሰማ ፡ ጊዜ ፥ ብዙም ፡ ቈንጃጅት ፡ ወደ ፡ ሱሳ ፡ ግንብ ፡ ወደ ፡ ሄጌ ፡ እጅ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፥ አስቴር ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ሴቶች ፡ ጠባ ፱ ቂው ፡ ወደ ፡ ሄጌ ፡ ተወሰደች ። ቆንጆይቱም ፡ ደስ ፡ አሰኘችው ፥ በእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ሞገስ ፡ አገኘች ፤ ቀበትዋንም ፡ ድርሻዋንም ፡ ከንጉሡም ፡ ቤት ፡ ልታገኝ ፡ የሚገባትን ፡ ሰባት ፡ ደንገጥሮች ፡ ፈጥኖ ፡ ሰጣት ፤ እርስዋንና ፡ ደንገጥሮችዋንም ፡ በሴቶች ፡ ቤት ፡ በተመረጠ ፡ ፲ ስፍራ ፡ አኖረ ። ይህንም ፡ እንዳትናገር ፡ መርዶክዮስ ፡ አዝዞአት ፡ ነበርና ፡ አስቴር ፡ ሕዝብ ፲፩ ዋንና ፡ ወገንዋን ፡ አልተናገረችም ። መርዶክዮስም ፡ የአስቴርን ፡ ደኅንነትና ፡ የሚሆንላትን ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ በሴቶች ፡ ቤት ፡ ወለል ፡ ትይዩ ፡ ይመላለስ ፡ ነበር ።

፲፪ የመንጻታቸውም ፡ ወራት ፡ ስድስት ፡ ወር ፡ ያህል ፡ በከርቤ ፡ ዘይት ፥ ስድስት ፡ ወርም ፡ በጣፋጭ ፡ ሽቱና ፡ በልዩ ፡ ልዩም ፡ በሚያነጻ ፡ ነገር ፡ ይፈጸም ፡ ነበርና ፡ እንደ ፡ ሴቶች ፡ ወግ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ወር ፡ እንዲሁ ፡ ከተደረገላት ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ አርጤክስስ ፡ ለመግባት ፡ የአንዳንዲቱ ፡ ቆንጆ ፡ ተራ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፥ ፲፫ በዚህ ፡ ወግ ፡ ቆንጆይቱ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ትገባ ፡ ነበር ፤ ከሴቶች ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቤት ፡ ለመውሰድ ፡ የምትሻውን ፡ ሁሉ ፡ ይሰጡአት ፡ ነበር ። ፲፬ ማታም ፡ ትገባ ፡ ነበር ፥ ሲነጋም ፡ ተመልሳ ፡ ወደ ፡ ሁለተኛው ፡ ሴቶች ፡ ቤት ፡ ቁባቶችን ፡ ወደሚጠብቅ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ጃንደረባ ፡ ወደ ፡ ጋይ ፡ ትመጣ ፡ ነበር ፤ ንጉሡም ፡ ያልፈለጋት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ በስምዋም ፡ ያልተጠራች ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ አት ፲፭ ገባም ፡ ነበር ። ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ትገባ ፡ ዘንድ ፡ የመርዶክዮስ ፡ አጎት ፡ የአቢካኢል ፡ ልጅ ፡ የአስቴር ፡ ተራ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ የሴቶች ፡ ጠባቂው ፡ የንጉሡ ፡ ጃንደረባ ፡ ሄጌ ፡ ከሚለው ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ አልፈለገችም ፡ ነበር ፤ አስቴርም ፡ በሚያዩአት ፡ ሁሉ ፡ ዓይን ፡ ሞገስ ፡ አግኝታ ፡ ነበርና ።

፲፮ አርጤክስስም ፡ በነገሠ ፡ በሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ አዳር ፡ በሚባለው ፡ በአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ወር ፡ አስቴር ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቤት ፡ ተወሰደች ። ፲፯ ንጉሡም ፡ ከሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ አስቴርን ፡ ወደደ ፥ በዓይኑም ፡ ከደናግል ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ሞገስንና ፡ መወደድን ፡ አገኘች ፤ የመንግሥቱንም ፡ ዘውድ ፡ በራስዋ ፡ ላይ ፡ አደረገ ፥ በአስ ፲፰ ጢንም ፡ ፋንታ ፡ አነገሣት ። ንጉሡም ፡ ስለ ፡ አስቴር ፡ ለባለምዋሎቹና ፡ ለአገልጋዮቹ ፡ ሁሉ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ ትልቅ ፡ ግብዣ ፡ አደረገ ፤ ለአገሮቹም ፡ ሁሉ ፡ ይቅርታ ፡ አደረገ ፥ እንደ ፡ ንጉሡም ፡ ለጋስነት ፡ መጠን ፡ ስጦታ ፡ ሰጠ ።

፲፱ ደናግሉም ፡ ዳግመኛ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡ መርዶክዮስ ፡ በንጉሡ ፡ በር ፡ ይቀመጥ ፡ ነበር ። ፳ አስቴርም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ እንዳደገችበት ፡ ጊዜ ፡ የመርዶክዮስን ፡ ትእዛዝ ፡ ታደርግ ፡ ነበርና ፡ መርዶክዮስ ፡ እንዳዘዛት ፡ አስቴር ፡ ወገ ፳፩ ንዋንና ፡ ሕዝብዋን ፡ አልተናገረችም ። በዚያም ፡ ወራት ፡ መርዶክዮስ ፡ በንጉሡ ፡ በር ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፡ ደጁን ፡ ከሚጠብቁት ፡ ከንጉሡ ፡ ጃንደረቦች ፡ ሁለቱ ፡ ገበታና ፡ ታራ ፡ ተቈጡ ፥ እጃቸውንም ፡ በንጉሡ ፡ በአርጤክ ፳፪ ስስ ፡ ላይ ፡ ያነሡ ፡ ዘንድ ፡ ፈለጉ ። ነገሩም ፡ ለመርዶክዮስ ፡ ተገለጠ ፥ እርሱም ፡ ለንግሥቲቱ ፡ ለአስቴር ፡ ነገራት ፤ አስቴርም ፡ በመርዶክዮስ ፡ ፳፫ ስም ፡ ለንጉሡ ፡ ነገረች ። ነገሩም ፡ ተመረመረ ፥ እንዲህም ፡ ሆኖ ፡ ተገኘ ፥ ሁለቱም ፡ በዛፍ ፡ ላይ ፡ ተሰቀሉ ፤ ያም ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ በታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ተጻፈ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ከዚህም ፡ ነገር ፡ በኋላ ፡ ንጉሡ ፡ አርጤክስስ ፡ የአጋጋዊውን ፡ የሐመዳቱን ፡ ልጅ ፡ ሐማን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገው ፥ አከበረውም ፥ ወንበሩንም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ከነበሩት ፡ አዛውንት ፡ ፪ ሁሉ ፡ በላይ ፡ አደረገለት ። ንጉሡም ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ እንዲሁ ፡ አዝዞ ፡ ነበርና ፡ በንጉሡ ፡ በር ፡ ያሉት ፡ የንጉሡ ፡ ባሪያዎች ፡ ሁሉ ፡ ተደፍተው ፡ ለሐማ ፡ ይሰግዱ ፡ ነበር ። መርዶክዮስ ፡ ፫ ግን ፡ አልተደፋም ፥ አልሰገደለትም ። በንጉሡም ፡ በር ፡ ያሉት ፡ የንጉሡ ፡ ባሪያዎች ፡ መርዶክዮስን ፡ — የንጉሡን ፡ ትእዛዝ ፡ ለምን ፡ ትተላለፋለህ ? አሉት ። ይህንም ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ፬ እየተናገሩ ፡ እርሱ ፡ ባልሰማቸው ፡ ጊዜ ፡ አይሁዳዊ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ነግሮአቸው ፡ ነበርና ፡ የመርዶክዮስ ፡ ነገር ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያዩ ፡ ፭ ዘንድ ፡ ለሐማ ፡ ነገሩት ። ሐማም ፡ መርዶክዮስ ፡ እንዳልተደፋለት ፡ እንዳልሰገደለትም ፡ ባየ ፡ ፮ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ። የመርዶክዮስን ፡ ወገን ፡ ነግረውት ፡ ነበርና ፡ በመርዶክዮስ ፡ ብቻ ፡ እጁን ፡ ይጭን ፡ ዘንድ ፡ በዓይኑ ፡ ተናቀ ፤ ሐማም ፡ በአር

ጤክስስ፡ መንግሥት፡ ሁሉ፡ የነበሩትን፡ የመርዶክዮስን፡ ሕዝብ፡ አይሁድን፡ ሁሉ፡ ሊያጠፋ፡ ፈለገ።

፯፤ በንጉሡም፡ በአርጤክስስ፡ በአሥራ፡ ሁለተኛው፡ ዓመት፡ ከመጀመሪያው፡ ወር፡ ከኒሳን፡ ጀምሮ፡ በየዕለቱና፡ በየወሩ፡ እስከ፡ አሥራ፡ ሁለተኛው፡ ወር፡ እስከ፡ አዳር፡ ድረስ፡ በሐማ፡ ፊት፡ ፉር፡ የተባለውን፡ ዕጣ፡ ይጥሉ፡ ነበር።

፰፤ ሐማም፡ ንጉሡን፡ አርጤክስስን፦ አንድ፡ ሕዝብ፡ በአሕዛብ፡ መካከል፡ በመንግሥትህ፡ አገሮች፡ ሁሉ፡ ተበትነዋል፤ ሕጋቸውም፡ ከሕዝቡ፡ ሁሉ፡ ሕግ፡ የተለየ፡ ነው፥ የንጉሡንም፡ ሕግ፡ አይጠብቁም፤ ንጉሡም፡ ይተዋቸው፡

፱፤ ዘንድ፡ አይገባውም። ንጉሡም፡ ቢፈቅድ፡ እንዲጠፉ፡ ይጻፍ፤ እኔም፡ ወደ፡ ንጉሡ፡ ግምጃ፡ ቤት፡ ያገቡት፡ ዘንድ፡ አሥር፡ ሺህ፡ መክሊት፡ ብር፡ የንጉሡን፡ ሥራ፡ በሚሠሩት፡

፲፤ እጅ፡ እመዝናለሁ፡ አለው። ንጉሡም፡ ቀለበቱን፡ ከእጁ፡ አወለቀ፥ ለአይሁድም፡ ጠላት፡ ለአጋጋዊው፡ ለሐመዳቱ፡ ልጅ፡ ለሐማ፡ ሰጠው።

፲፩፤ ንጉሡም፡ ሐማን፦ ደስ፡ የሚያሰኝህን፡ ነገር፡ ታደርግባቸው፡ ዘንድ፡ ብሩም፡ ሕዝቡም፡ ለአንተ፡ ተሰጥቶሃል፡ አለው።

፲፪፤ በመጀመሪያውም፡ ወር፡ ከወሩም፡ በአሥራ፡ ሦስተኛው፡ ቀን፡ የንጉሡ፡ ጸሐፊዎች፡ ተጠሩ፤ ከህንድ፡ ጀምሮ፡ እስከ፡ ኢትዮጵያ፡ ድረስ፡ ወዳሉ፡ መቶ፡ ሀያ፡ ሰባት፡ አገሮች፥ በየአገሩ፡ ወዳሉ፡ ሹማምትና፡ አለቆች፡ ወደ፡ አሕዛብም፡ ሁሉ፡ ገዢዎች፡ እንደ፡ ቋንቋቸው፡ በንጉሡ፡ በአርጤክስስ፡ ቃል፡ ሐማ፡ እንዳዘዘ፡ ተጻፈ፥

፲፫፤ በንጉሡም፡ ቀለበት፡ ታተመ። በአሥራ፡ ሁለተኛው፡ ወር፡ በአዳር፡ በአሥራ፡ ሦስተኛው፡ ቀን፡ አይሁድን፡ ሁሉ፥ ልጆችንና፡ ሽማግሌዎችን፥ ሕፃናቶችንና፡ ሴቶችን፥ በአንድ፡ ቀን፡ ያጠፉና፡ ይገድሉ፡ ዘንድ፥ ይደመስሱም፡ ዘንድ፥ ምርኮአቸውንም፡ ይዘርፉ፡ ዘንድ፡ ደብዳቤዎች፡ በመልእክተኞች፡ እጅ፡ ወደ፡ ንጉሡ፡ አገሮች፡ ሁሉ፡ ተላኩ።

፲፬፤ በዚያም፡ ቀን፡ ይዘጋጁ፡ ዘንድ፡ የደብዳቤው፡ ቅጅ፡ በየአገሩ፡ ላሉ፡ አሕዛብ፡ ሁሉ፡ ታወጀ።

፲፭፤ መልእክተኞቹም፡ በንጉሡ፡ ትእዛዝ፡ እየቸኰሉ፡ ሄዱ፥ አዋጁም፡ በሱሳ፡ ግንብ፡ ተነገረ። ንጉሡና፡ ሐማ፡ ሊጠጡ፡ ተቀመጡ፤ ከተማይቱ፡ ሱሳ፡ ግን፡ ተደናገጠች።

## ምዕራፍ፡ ፬።

፩፤ መርዶክዮስም፡ የተደረገውን፡ ሁሉ፡ ባወቀ፡ ጊዜ፡ ልብሱን፡ቀደደ፥ ማቅም፡ ለበሰ፡ አመድም፡ ነሰነሰ፥ ወደ፡ ከተማይቱም፡ መካከል፡ ወጣ፥ ታላቅም፡ የመረረ፡ ጩኸት፡ ጮኸ።

፪፤ ማቅም፡ ለብሶ፡ በንጉሥ፡ በር፡ መግባት፡ አይገባም፡ ነበርና፡ እስከ፡ ንጉሡ፡ በር፡ አቅራቢያ፡ መጣ።

፫፤ የንጉሡም፡ ትእዛዝና፡ አዋጅ፡ በደረሰበት፡ አገር፡ ሁሉ፡ በአይሁድ፡ ላይ፡ ታላቅ፡ ኀዘንና፡ ጾም፡ ልቅሶና፡ ዋይታም፡ ሆነ፡ ብዙዎችም፡ ማቅና፡ አመድ፡ አነጠፉ።

፬፤ የአስቴርም፡ ደንገጥሮችዋና፡ ጃንደረቦችዋ፡ መጥተው፡ ነገሩአት፥ ንግሥቲቱም፡ እጅግ፡ አዘነች፤ ማቁንም፡ ለውጦ፡ ልብስ፡ ይለብስ፡ ዘንድ፡ ለመርዶክዮስ፡ ሰደደችለት፤ እርሱ፡ ግን፡ አልተቀበለም።

፭፤ አስቴርም፡ ያገለግላት፡ ዘንድ፡ ንጉሡ፡ ያቆመውን፡ አክራትዮስን፡ ጠራች፡ እርሱም፡ ከጃንደረቦች፡ አንዱ፡ ነበረ፥ እርስዋም፡ ይህ፡ ነገር፡ ምንና፡ ምን፡ እንደ፡ ሆነ፡ ያስታውቃት፡ ዘንድ፡ ወደ፡ መርዶክዮስ፡ እንዲሄድ፡ አዘዘችው።

፮፤ አክራትዮስም፡ በንጉሥ፡ በር፡ ፊት፡ ወደ፡ ነበረችው፡ ወደ፡ ከተማይቱ፡ አደባባይ፡ ወደ፡ መርዶክዮስ፡ ወጣ።

፯፤ መርዶክዮስም፡ የተደረገውን፡ ሁሉ፥ አይሁድንም፡ ለማጥፋት፡ ሐማ፡ በንጉሡ፡ ግምጃ፡ ቤት፡ ይመዝን፡ ዘንድ፡ የተናገረውን፡ የብሩን፡ ቍጥር፡ ነገረው።

፰፤ ለአስቴርም፡ እንዲያሳያት፡ ለመጥፋታቸው፡ በሱሳ፡ የተነገረውን፡ የአዋጁን፡ጽሕፈት፡ ቅጅ፡ ሰጠው፤ ወደ፡ ንጉሡም፡ ገብታ፡ ስለ፡ ሕዝብዋ፡ ትለምነውና፡ ትማልደው፡ ዘንድ፡ እንዲነግራትና፡ እንዲያዝዛት፡ ነገረው።

፱፤ አክራትዮስም፡ መጥቶ፡ የመርዶክዮስን፡ ቃል፡ ለአስቴር፡ ነገራት።

፲፤ አስቴርም፡ አክራትዮስን፡ ተናገረችው፥ ለመርዶክዮስም፡ እንዲህ፡ የሚል፡ መልእክት፡ ሰጠችው፦

፲፩፤ የንጉሡ፡ ባሪያዎችና፡ በአገሮችም፡ የሚኖሩ፡ ሕዝብ፡ ሁሉ፡ ወንድ፡ ወይም፡ ሴት፡ ቢሆን፡ ሳይጠራ፡ ወደ፡ ንጉሡ፡ ወደ፡ ውስጠኛው፡ ወለል፡ የሚገባ፡ ሁሉ፥ በሕይወት፡ ይኖር፡ ዘንድ፡ ንጉሡ፡ የወርቁን፡ ዘንግ፡ ካልዘረጋለት፡ በቀር፥ እርሱ፡ ይሞት፡ ዘንድ፡ ሕግ፡ እንዳለ፡ ያውቃሉ፤ እኔ፡ ግን፡ ወደ፡ ንጉሡ፡ ለመግባት፡ ይህን፡ ሠላሳውን፡ ቀን፡ አልተጠራሁም።

፲፪፤ አክራትዮስም፡ የአስቴርን፡ ቃል፡ ለመርዶክዮስ፡ ነገረው።

፲፫፤ መርዶክዮስም፡ አክራትዮስን፦ ሂድና፡ ለአስቴር፡ እንዲህ፡ በላት፡ አለው፦ አንቺ፦ በንጉሥ፡ ቤት፡ ስለ፡ ሆንሁ፡ ከአይሁድ፡ ሁሉ፡ ይልቅ፡ እድናለሁ፡ ብለሽ፡ በልብሽ፡ አታስቢ።

፲፬፤ በዚህ፡ ጊዜ፡ ቸል፡ ብትዪ፡ ዕረፍትና፡ መዳን፡ ለአይሁድ፡ ከሌላ፡ ስፍራ፡ ይሆንላቸዋል፥ አንቺና፡ የአባትሽ፡ ቤት፡ ግን፡ ትጠፋላችሁ፤ ደግሞስ፡ ወደ፡ መንግሥት፡ የመጣሽው፡ እንደዚህ፡ ላለው፡ ጊዜ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ማን፡ ያውቃል?

፲፭፤ አስቴርም፡ እንዲህ፡ ብሎ፡ ለመርዶክዮስ፡ እንዲመልስ፡ አዘዘችው፦

፲፮፤ ሄደህ፡ በሱሳ፡ ያሉትን፡ አይሁድ፡ ሁሉ፡ ሰብስብ፥ ለእኔም፡ ጹሙ፤ ሦስት፡ ቀን፡ ሌሊቱንና፡ ቀኑን፡ አትብሉም፥ አትጠጡም፤ እኔና፡ ደንገጥሮቼ፡ ደግሞ፡ እንዲሁ፡ እንጾማለን፤ ምንም፡ እንኳ፡ ያለ፡ ሕግ፡ ቢሆን፡ ወደ፡ ንጉሡ፡ እገባለሁ፤ ብጠፋም፡ እጠፋለሁ።

፲፯፤ መርዶክዮስም፡ ሄዶ፡ አስቴር፡ እንዳዘዘችው፡ ሁሉ፡ አደረገ።

## መዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ አስቴር ፡ ልብሰ ፡ መን
ግሥትዋን ፡ ለብሳ ፡ በንጉሡ ፡ ቤት ፡ ትይዩ ፡
በንጉሡ ፡ ቤት ፡ በውስጠኛው ፡ ወለል ፡ ቆመች ፤
ንጉሡም ፡ በቤቱ ፡ መግቢያ ፡ ትይዩ ፡ በቤተ ፡
መንግሥቱ ፡ ውስጥ ፡ በንጉሡ ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡
፪ ተቀምጦ ፡ ነበር ። ንጉሡም ፡ ንግሥቲቱ ፡ አስ
ቴር ፡ በወለሉ ፡ ላይ ፡ ቆማ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ በዓይኑ ፡
ሞገስ ፡ አገኘች ፤ ንጉሡም ፡ በእጁ ፡ የነበረውን ፡
የወርቁን ፡ ዘንግ ፡ ለአስቴር ፡ ዘረጋላት ፤ አስቴ
ርም ፡ ቀርባ ፡ የዘንጉን ፡ ጫፍ ፡ ነካች ።
፫ ንጉሡም ፡— ንግሥት ፡ አስቴር ፡ ሆይ ፥ የምት
ለምኚኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ? የምትሺውስ ፡ ምን
ድር ፡ ነው ? እስከ ፡ መንግሥቴ ፡ እኩሌታ ፡
፬ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ ይሰጥሻል ፡ አላት ። አስቴርም ፡—
ለንጉሡ ፡ መልካም ፡ ሆኖ ፡ ቢታይ ፡ ንጉሡ ፡
ወዳዘጋጀሁለት ፡ ግብዣ ፡ ከሐማ ፡ ጋር ፡ ዛሬ ፡
፭ ይምጣ ፡ አለች ። ንጉሡም ፡— አስቴር ፡ እንዳ
ለች ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ ሐማን ፡ አስቸኩሉት ፡
አለ ። ንጉሡና ፡ ሐማ ፡ አስቴር ፡ ወዳዘጋጀ
፮ ችው ፡ ግብዣ ፡ መጡ ። ንጉሡም ፡ በወይኑ ፡
ጠጅ ፡ ግብዣ ፡ ሳለ ፡ አስቴርን ፡— የምትሺው ፡
ምንድር ፡ ነው ? ይሰጥሻል ፤ ልመናሽስ ፡ ምን
ድር ፡ ነው ? እስከ ፡ መንግሥቴ ፡ እኩሌታ ፡
፯ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ ይደረግልሻል ፡ አላት ። አስቴ
ርም ፡ መልሳ ፡— ልመናዬና ፡ የምሻው ፡ ነገር ፡
፰ ይህ ፡ ነው ፤ በንጉሡ ፡ ዘንድ ፡ ሞገስ ፡ አግኝቼ ፡
እንደ ፡ ሆነ ፥ ልመናዬንም ፡ ይፈጽም ፡ ዘንድና ፡
የምሻውን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ንጉሡን ፡ ደስ ፡
ቢያሰኘው ፥ ንጉሡና ፡ ሐማ ፡ ወደማዘጋጅላ
ቸው ፡ ግብዣ ፡ ይምጡ ፤ እንደ ፡ ንጉሡም ፡
ነገር ፡ ነገ ፡ አደርጋለሁ ፡ አለች ።
፱ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሐማ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ በል
ቡም ፡ ተደስቶ ፡ ወጣ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ መርዶክዮስ ፡
በንጉሡ ፡ በር ፡ ያለ ፡ መነሣትና ፡ ያለ ፡ መናወጥ ፡
ተቀምጦ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ሐማ ፡ በመርዶክዮስ ፡
፲ ላይ ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ። ሐማ ፡ ግን ፡ ታግሦ ፡
ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ፤ ልኮም ፡ ወዳጆቹንና ፡ ሚስ
፲፩ ቱን ፡ ዞሳራን ፡ አስጠራ ። ሐማም ፡ የሀብቱን ፡
ክብርና ፡ የልጆቹን ፡ ብዛት ፥ ንጉሡም ፡ ያከበረ
በትን ፡ ክብር ፡ ሁሉ ፥ በንጉሡም ፡ አዛውንትና ፡
ባሪያዎች ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እንዳደረገው ፡
፲፪ አጫወታቸው ። ሐማም ፡— ንግሥቲቱ ፡ አስ
ቴር ፡ ወዳዘጋጀችው ፡ ግብዣ ፡ ከእኔ ፡ በቀር ፡
ከንጉሡ ፡ ጋር ፡ ማንንም ፡ አልጠራችም ፤ ደግሞ ፡
ነገ ፡ ከንጉሡ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ተጠርቻ
፲፫ ለሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ አይሁዳዊው ፡ መርዶክዮስ ፡
በንጉሡ ፡ በር ፡ ተቀምጦ ፡ ካየሁ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡
፲፬ ለእኔ ፡ ምንምን ፡ አይጠቅምም ፡ አለ ። ሚስ
ቱም ፡ ዞሳራና ፡ ወዳጆቹ ፡ ሁሉ ፡— ቁመቱ ፡
አምሳ ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፡ ግንድ ፡ ይደረግ ፥ ነገም ፡
መርዶክዮስ ፡ ይሰቀልበት ፡ ዘንድ ፡ ለንጉሡ ፡
ተናገር ፤ ደስም ፡ ብሎህ ፡ ከንጉሡ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡
ግብዣው ፡ ግባ ፡ አሉት ። ነገራቸውም ፡ ሐማን ፡
ደስ ፡ አሰኘው ፥ ግንዱንም ፡ አስደረገ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ በዚያም ፡ ሌሊት ፡ እንቅልፍ ፡ ከንጉሡ ፡ ሸሸ ፤
የዘመኑንም ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡
፪ አዘዘ ፥ በንጉሡም ፡ ፊት ፡ ተነበበ ። ደጁንም ፡
ከሚጠብቁት ፡ ከንጉሡ ፡ ጃንደረቦች ፡ ሁለቱ ፡
ገበታና ፡ ታራ ፡ እጃቸውን ፡ በንጉሡ ፡ በአርጤ
ክስስ ፡ ላይ ፡ ያነሡ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ፈለጉ ፥ መር
፫ ዶክዮስ ፡ እንደ ፡ ነገረው ፡ ተጽፎ ፡ ተገኘ ። ንጉ
ሡም ፡— ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ለመርዶክዮስ ፡ ምን ፡
ክብርና ፡ በጎነት ፡ ተደረገለት ? አለ ። ንጉሡ
ንም ፡ የሚያገለግሉ ፡ ብላቴኖች ፡— ምንም ፡
፬ አልተደረገለትም ፡ አሉት ። ንጉሡም ፡— በአ
ደባባዩ ፡ ማን ፡ አለ ? አለ ። ሐማም ፡ ባዘጋጀው ፡
ግንድ ፡ ላይ ፡ መርዶክዮስን ፡ ለማሰቀል ፡ ለን
ጉሡ ፡ ይናገር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቤት ፡
፭ ወደ ፡ ውጭው ፡ አዳራሽ ፡ ገብቶ ፡ ነበር ። የንጉ
ሡም ፡ ብላቴኖች ፡— እነሆ ፡ ሐማ ፡ በአዳራሹ ፡
ቆሞአል ፡ አሉት ። ንጉሡም ፡— ይግባ ፡ አለ ።
፮ ሐማም ፡ ገባ ፤ ንጉሡም ፡— ንጉሡ ፡ ሊያከብ
ረው ፡ ለሚወድደው ፡ ሰው ፡ ምን ፡ ይደረግለ
ታል ? አለው ። ሐማም ፡ በልቡ ፡— ንጉሡ ፡
ከእኔ ፡ ይልቅ ፡ ማንን ፡ ያከብር ፡ ዘንድ ፡ ይወድ
፯ ዳል ? አለ ። ሐማም ፡ ንጉሡን ፡ እንዲህ ፡
አለው ፡— ንጉሡ ፡ ያከብረው ፡ ዘንድ ፡ ለሚወ
፰ ድደው ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ይደረግ ፤ ንጉሡ ፡ የለ
በሰው ፡ የክብር ፡ ልብስ ፥ ንጉሡም ፡ የተቀመጠ
በት ፡ ፈረስ ፡ ይምጣለት ፥ የንጉሡም ፡ ዘውድ ፡
፱ በራሱ ፡ ላይ ፡ ይደረግ ፤ ልብሱንና ፡ ፈረሱንም ፡
ከንጉሡ ፡ አዛውንት ፡ በዋነኛው ፡ እጅ ፡ ያስረ
ክቡት ፤ ንጉሡም ፡ ያከብረው ፡ ዘንድ ፡ የሚወ
ድደውን ፡ ሰው ፡ ያልብሱት ፤ በፈረሱም ፡ ላይ ፡
አስቀምጠውት ፡ በከተማይቱ ፡ አደባባይ ፡ ያሳል
ፉት ፤ በፊቱም ፡— ንጉሡ ፡ ያከብረው ፡ ዘንድ ፡
ለሚወድደው ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ይደረግለታል ፡
ተብሎ ፡ አዋጅ ፡ ይነገር ።
፲ ንጉሡም ፡ ሐማን ፡— ፍጠን ፥ እንደ ፡ ተናገ
ርኸውም ፡ ልብሱንና ፡ ፈረሱን ፡ ውሰድ ፤ በንጉ
ሡም ፡ በር ፡ ለሚቀመጠው ፡ አይሁዳዊ ፡ ለመ
ርዶክዮስ ፡ እንዲሁ ፡ አድርግለት ፤ ከተናገርኸ
፲፩ ውም ፡ ሁሉ ፡ ምንም ፡ አይቅር ፡ አለው ። ሐማም ፡
ልብሱንና ፡ ፈረሱን ፡ ወሰደ ፥ መርዶክዮስንም ፡
አለበሰው ፥ በፈረሱም ፡ ላይ ፡ አስቀመጠው ፥
በከተማይቱም ፡ አደባባይ ፡ በፊቱ ፡ አሳለፈው ።
በፊቱም — ንጉሡ ፡ ያከብረው ፡ ዘንድ ፡ ለሚ
ወድደው ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ይደረግለታል ፡ ብሎ ፡
፲፪ አዋጅ ፡ ነገረ ። መርዶክዮስም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡
በር ፡ ተመለሰ ። ሐማ ፡ ግን ፡ አዝኖና ፡ ራሱን ፡
፲፫ ተከናንቦ ፡ ቸኵሎ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ። ሐማም ፡
ለሚስቱ ፡ ለዞሳራና ለወዳጆቹ ፡ ሁሉ ፡ ያገኘ
ውን ፡ ሁሉ ፡ አጫወታቸው ። ጥበበኞቹና ፡
ሚስቱ ፡ ዞሳራም ፡— በፊቱ ፡ መውደቅ ፡ የጀ

መርህለት ፡ መርዶክዮስ ፡ ከአይሁድ ፡ ወገን ፡ የሆነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በፊቱ ፡ ፈጽሞ ፡ ትወድቃ ለህ ፡ እንጂ ፡ አታሸንፈውም ፡ አሉት ። ፲፬ እነር ሱም ፡ ሲናገሩት ፡ ሳሉ ፡ እነሆ ፡ የንጉሡ ፡ ጃን ደረቦች ፡ መጡ ፥ አስቴርም ፡ ወዳዘጋጀችው ፡ ግብዣ ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ ሐማን ፡ አስቸኰሉት ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ንጉሡና ፡ ሐማም ፡ ከንግሥቲቱ ፡ ከአስቴር ፡ ጋር ፡ ለመጠጣት ፡ መጡ ። ፪ በሁለተኛውም ፡ ቀን ፡ ንጉሡ ፡ በወይኑ ፡ ጠጅ ፡ ግብዣ ፡ ሳለ ፡ አስ ቴርን ፦ ንግሥት ፡ አስቴር ፡ ሆይ ፥ የምትለም ኚኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ይሰጥሻል ፤ የምትሺ ውስ ፡ ምንድር ፡ ነው ? እስከ ፡ መንግሥቴ ፡ እኩሌታ ፡ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ ይደረግልሻል ፡ አላት ። ፫ ንግሥቲቱም ፡ አስቴር ፡ መልሳ ፦ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ሞገስ ፡ አግኝቼ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ንጉሡንም ፡ ደስ ፡ ቢያሰኘው ፥ ሕይወቴ ፡ በልመናዬ ፡ ሕዝቤም ፡ በመሻቴ ፡ ፬ ይሰጠኝ ፤ እኔና ፡ ሕዝቤ ፡ ለመጥፋትና ፡ ለመገደል ፡ ለመደምሰስም ፡ ተሸጠናልና ። ባሪያዎች ፡ ልንሆን ፡ ተሸጠን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ዝም ፡ ባልሁ ፡ ነበር ፤ የሆነ ፡ ሆኖ ፡ ጠላቱ ፡ የንጉሡን ፡ ጉዳት ፡ ለማቅናት ፡ ባልቻለም ፡ ነበር ፡ አለች ። ፭ ንጉሡም ፡ አርጤክስስ ፡ ንግሥ ቲቱን ፡ አስቴርን ፦ ይህን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ በልቡ ፡ የደፈረ ፡ ማን ፡ ነው ? እርሱስ ፡ ወዴት ፡ ነው ? ብሎ ፡ ተናገራት ። ፮ አስቴርም ፦ ያ ፡ ጠላ ትና ፡ ባለጋራ ፡ ሰው ፡ ክፉው ፡ ሐማ ፡ ነው ፡ አለች ። ሐማም ፡ በንጉሡና ፡ በንግሥቲቱ ፡ ፊት ፡ ደነገጠ ። ፯ ንጉሡም ፡ ተቈጥቶ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ከመጠጣቱ ፡ ተነሣ ፥ ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ቤት ፡ አታክልት ፡ ውስጥ ፡ ሄደ ። ሐማም ፡ ከን ጉሡ ፡ ዘንድ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ታሰበበት ፡ አይቶአልና ፡ ከንግሥቲቱ ፡ ከአስቴር ፡ ሕይወ ቱን ፡ ይለምን ፡ ዘንድ ፡ ቆመ ። ፰ ንጉሡም ፡ ከቤቱ ፡ አታክልት ፡ ወደ ፡ ወይን ፡ ጠጁ ፡ ግብዣ ፡ ስፍራ ፡ ተመለሰ ፤ ሐማም ፡ አስቴር ፡ ባለችበት ፡ አልጋ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ነበር ። ንጉሡም ፦ ደግሞ ፡ በቤቴ ፡ በእኔ ፡ ፊት ፡ ንግሥቲቱን ፡ ይጋ ፋታልን ? አለ ። ይህም ፡ ቃል ፡ ከንጉሡ ፡ አፍ ፡ ፱ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ የሐማን ፡ ፊት ፡ ሸፈኑት ። በንጉ ሡም ፡ ፊት ፡ ካሉት ፡ ጃንደረቦች ፡ አንዱ ፡ ሐርቦና ፦ እነሆ ፡ ሐማ ፡ ለንጉሡ ፡ በጎ ፡ ለተ ናገረው ፡ ለመርዶክዮስ ፡ ያሠራው ፡ ርዝመቱ ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ የሆነው ፡ ግንድ ፡ በሐማ ፡ ቤት ፡ ተተክሎአል ፡ አለ ። ንጉሡም ፦ በእርሱ ፡ ፲ ላይ ፡ ስቀሉት ፡ አለ ። ሐማንም ፡ ለመርዶክ ዮስ ፡ ባዘጋጀው ፡ ግንድ ፡ ላይ ፡ ሰቀሉት ፤ በዚ ያም ፡ ጊዜ ፡ የንጉሡ ፡ ቍጣ ፡ በረደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ በዚያም ፡ ቀን ፡ ንጉሡ ፡ አርጤክስስ ፡ የአይ ሁድን ፡ ጠላት ፡ የሐማን ፡ ቤት ፡ ለንግሥቲቱ ፡ ለአስቴር ፡ ሰጠ ። አስቴርም ፡ ለእርስዋ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ነግራው ፡ ነበርና ፡ መርዶክዮስ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ፊት ፡ ገባ ። ፪ ንጉሡም ፡ ከሐማ ፡ ያወለቀውን ፡ ቀለበቱን ፡ አወጣ ፥ ለመርዶክዮ ስም ፡ ሰጠው ። አስቴርም ፡ በሐማ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ መርዶክዮስን ፡ ሾመች ።

፫ አስቴርም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ ተና ገረች ፤ በእግሩም ፡ ላይ ፡ ወድቃ ፡ እያለቀሰች ፡ የአጋጋዊውን ፡ የሐማን ፡ ክፋትና ፡ በአይሁድ ፡ ላይ ፡ የተተነኰለውን ፡ ተንኰል ፡ ይሽር ፡ ዘንድ ፡ ለመነችው ። ፬ ንጉሡም ፡ የወርቁን ፡ ዘንግ ፡ ለአ ስቴር ፡ ዘረጋላት ፤ አስቴርም ፡ ተነሥታ ፡ በን ጉሡ ፡ ፊት ፡ ቆመችና ፦ ፭ ንጉሡን ፡ ደስ ፡ ቢያ ሰኘው ፥ በፊቱም ፡ ሞገስ ፡ አግኝቼ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ይህም ፡ ነገር ፡ በፊቱ ፡ ቅን ፡ ቢሆን ፥ እኔም ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ተወድጄ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ አጋ ጋዊው ፡ የሐመዳቱ ፡ ልጅ ፡ ሐማ ፡ በንጉሡ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ያሉትን ፡ አይሁድ ፡ ለማጥፋት ፡ የጻፈው ፡ ተንኰል ፡ ይገለበጥ ፡ ዘንድ ፡ ይጻፍ ። ፮ እኔ ፡ በሕዝቤ ፡ ላይ ፡ የሚወርደውን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አይ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ እችላለሁ ? ወይስ ፡ የዘ መዶቼን ፡ ጥፋት ፡ አይ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ እች ላለሁ ? አለች ። ፯ ንጉሡም ፡ አርጤክስስ ፡ ንግ ሥቲቱን ፡ አስቴርንና ፡ አይሁዳዊውን ፡ መርዶ ክዮስን ፦ እነሆ ፡ የሐማን ፡ ቤት ፡ ለአስቴር ፡ ሰጥቻለሁ ፥ እርሱም ፡ እጆቹን ፡ በአይሁድ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ዘረጋ ፡ በግንድ ፡ ላይ ፡ ተሰቀለ ። ፰ በንጉሡ ፡ ስም ፡ የተጻፈና ፡ በንጉሡ ፡ ቀለበት ፡ የታተመ ፡ አይገለበጥምና ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኛችሁን ፡ በንጉሡ ፡ ስም ፡ ስለ ፡ አይሁድ ፡ ጻፉ ፥ በንጉሡም ፡ ቀለበት ፡ አትሙ ፡ አላቸው ።

፱ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኒሳን ፡ በተባለው ፡ በመጀ መሪያው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በሀያ ፡ ሦስተኛው ፡ ቀን ፡ የንጉሡ ፡ ጸሐፊዎች ፡ ተጠሩ ፤ መርዶክ ዮስም ፡ ስለ ፡ አይሁድ ፡ እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ፡ ከህንድ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ድረስ ፡ በመቶ ፡ ሀያ ፡ ሰባቱ ፡ አገሮች ፡ ላሉ ፡ ሹማም ትና ፡ አለቆች ፡ አዛውንትም ፡ ለእያንዳንዱም ፡ አገር ፡ እንደ ፡ ጽሕፈቱ ፡ ለእያንዳንዱም ፡ ሕዝብ ፡ እንደ ፡ ቋንቋው ፡ ለአይሁድም ፡ እንደ ፡ ጽሕፈ ታቸውና ፡ እንደ ፡ ቋንቋቸው ፡ ተጻፈ ። ፲ በንጉ ሡም ፡ በአርጤክስስ ፡ ስም ፡ አስጻፈው ፥ በን ጉሡም ፡ ቀለበት ፡ አሳተመው ፤ ደብዳቤውንም ፡ በንጉሡ ፡ ፈረስ ፡ ቤት ፡ በተወለዱት ፥ ለንጉ ሡም ፡ አገልግሎት ፡ በተለዩ ፡ በፈጣን ፡ ፈረ ሶች ፡ በተቀመጡ ፡ መልእክተኞች ፡ እጅ ፡ ሰደ ደው ። ፲፩ በዚያም ፡ ደብዳቤ ፡ በከተሞቹ ፡ ሁሉ ፡ የሚኖሩት ፡ አይሁድ ፡ እንዲሰበሰቡ ፥ ለሕይወ ታቸውም ፡ እንዲቆሙ ፥ በጥል ፡ የሚነሡባቸ ውን ፡ የሕዝቡንና ፡ የአገሩን ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ ከሕፃናቶቻቸውና ፡ ከሴቶቻቸው ፡ ጋር ፡ እንዲ ያጠፉና ፡ እንዲገድሉ ፡ እንዲደመስሱም ፥ ምር ኮአቸውንም ፡ እንዲዘርፉ ፡ ንጉሡ ፡ ፈቀደላ

፲፪ ቸው ። ይህም ፡ አዳር ፡ በሚባለው ፡ በአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ ሦስተኛው ፡ ቀን ፡ በንጉሡ ፡ በአርጤክስስ ፡ አገሮች ፡ ሁሉ ፡ በአንድ ፡ ቀን ፡ እንዲሆን ፡ ነው ።

፲፫ አይሁድም ፡ ጠላቶቻቸውን ፡ እንዲበቀሉ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ይዘጋጁ ፡ ዘንድ ፡ የደብዳቤው ፡ ፲፬ ቅጅ ፡ በየአገሩ ፡ ላሉ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ታወጀ ። ለንጉሡ ፡ አገልግሎት ፡ በተለዩ ፡ በፈጣን ፡ ፈረሶች ፡ የተቀመጡት ፡ መልእክተኞች ፡ በንጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ ተርበትብተውና ፡ ቸኵለው ፡ ወጡ ፤ አዋጁም ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡ ተነገረ ።

፲፭ መርዶክዮስም ፡ በሰማያዊና ፡ በነጭ ፡ ሐር ፡ የተሠራውን ፡ የንጉሡን ፡ የክብር ፡ ልብስ ፡ ለብሶ ፡ ታላቅም ፡ የወርቅ ፡ አክሊል ፡ ደፍቶ ፡ ከጥሩ ፡ በፍታና ፡ ከሐምራዊ ፡ ግምጃ ፡ የተሠራ ፡ መጐናጸፊያ ፡ ተጐናጽፎ ፡ ከንጉሡ ፡ ፊት ፡ ወጣ ፤ የሱሳም ፡ ከተማ ፡ ደስ ፡ አላት ፥ እልልም ፡ ፲፮ አለች ። ለአይሁድም ፡ ብርሃንና ፡ ደስታ ፡ ተድ ፲፯ ላና ፡ ክብርም ፡ ሆነ ። የንጉሡም ፡ ትእዛዝና ፡ አዋጅ ፡ በደረሰበት ፡ አገርና ፡ ከተማ ፡ ሁሉ ፡ ለአይሁድ ፡ ደስታና ፡ ተድላ ፥ የግብዣም ፡ ቀን ፡ መልካምም ፡ ቀን ፡ ሆነ ። አይሁድንም ፡ መፍራት ፡ ስለ ፡ ወደቀባቸው ፡ ከምድር ፡ አሕዛብ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ አይሁድ ፡ ሆኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ አዳር ፡ በሚባለውም ፡ በአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአሥራ ፡ ሦስተኛው ፡ ቀን ፥ የንጉሡ ፡ ትእዛዝና ፡ አዋጅ ፡ ሊፈጸምበት ፡ በነበረው ፡ ቀን ፥ የአይሁድ ፡ ጠላቶች ፡ ሊሠለጥኑባቸው ፡ በነበረው ፡ ቀን ፥ አይሁድ ፡ በጠላቶቻቸው ፡ ላይ ፡ እንዲሠለጥኑ ፡ ነገሩ ፡ ተገለበጠ ። ፪ አይሁድም ፡ ክፉታቸውን ፡ በሚሹት ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ እጃቸውን ፡ ይዘረጉ ፡ ዘንድ ፡ በንጉሡ ፡ በአርጤክስስ ፡ አገሮች ፡ ሁሉ ፡ በነበሩ ፡ ከተሞቻቸው ፡ ውስጥ ፡ ተሰበሰቡ ፤ እነርሱንም ፡ መፍራት ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ነበርና ፡ እነርሱን ፡ የሚቃወም ፡ ሰው ፡ አልነበረም ። ፫ መርዶክዮስን ፡ መፍራት ፡ በላያቸው ፡ ስለ ፡ ወደቀ ፡ በየአገሩ ፡ የነበሩ ፡ አዛውንትና ፡ ሹማምቶች ፡ አለቆችም ፥ የንጉሡንም ፡ ሥራ ፡ የሚ ፬ ሠሩቱ ፡ ሁሉ ፡ አይሁድን ፡ አገዙ ። ያ ፡ ሰው ፡ መርዶክዮስ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እያለ ፡ ስለ ፡ ሄደ ፡ በንጉሡ ፡ ቤት ፡ ታላቅ ፡ ሆኖ ፡ ነበርና ፥ የመርዶክዮስም ፡ ዝና ፡ በየአገሩ ፡ ሁሉ ፡ ተሰምቶ ፡ ፭ ነበርና ። አይሁድም ፡ ጠላቶቻቸውን ፡ ሁሉ ፡ በሰይፍ ፡ እየመቱ ፡ ገደሉአቸው ፥ አጠፉአቸውም ፤ በሚጠሉአቸውም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ወደዱ ፡ ፮ አደረጉባቸው ። አይሁድም ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ያህል ፡ ሰዎች ፡ ገደሉ ፡ አጠ ፯፡፰ ፉም ። ፈርሰኔስ ፥ ደልፎን ፥ ፋስጋ ፥ ፋረዳታ ፥ ፱ በርያ ፥ ሰርበካ ፥ መርመሲማ ፥ ሩፋዮስ ፥ አርሳ ፲ ዮስ ፥ ዛቡታዮስ ፡ የሚባሉትን ፥ የሐመዳቱን ፡ ልጅ ፡ የአይሁድን ፡ ጠላት ፡ አሥሩን ፡ የሐማን ፡ ልጆች ፡ ገደሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ብዝበዛው ፡ እጃቸውን ፡ አልዘረጉም ።

፲፩ በዚያም ፡ ቀን ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡ የተገደሉት ፡ ፲፪ ሰዎች ፡ ቍጥር ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ መጣ ። ንጉሡም ፡ ንግሥቲቱን ፡ አስቴርን ፦ አይሁድ ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ሰዎችንና ፡ አሥሩን ፡ የሐማ ፡ ልጆች ፡ ገደሉ ፡ አጠፉአቸውም ፤ በቀሩትስ ፡ በንጉሡ ፡ አገሮች ፡ እንዴት ፡ አድርገው ፡ ይሆን ፤ አሁንስ ፡ ልመናሽ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ይሰጥሻል ፤ ሌላስ ፡ የምትሺው ፡ ምንድር ፡ ነው ? ይደረጋል ፡ አላት ። አስቴ ፲፫ ርም ፦ ንጉሡን ፡ ደስ ፡ ቢያሰኘው ፡ በሱሳ ፡ የሚኖሩ ፡ አይሁድ ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡ ተደረገው ፡ ትእዛዝ ፡ ነገ ፡ ደግሞ ፡ ያድርጉ ፤ አሥሩም ፡ የሐማ ፡ ልጆች ፡ በግንድ ፡ ላይ ፡ ይሰቀሉ ፡ አለች ። ፲፬ ንጉሡም ፡ ይህ ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ አዋጅም ፡ በሱሳ ፡ ተነገረ ፤ አሥሩንም ፡ የሐማን ፡ ልጆች ፡ ሰቀሉ ። ፲፭ በሱሳም ፡ የነበሩ ፡ አይሁድ ፡ አዳር ፡ በሚባለው ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ ደግሞ ፡ ተሰብስበው ፡ በሱሳ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ያህል ፡ ሰዎች ፡ ገደሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ብዝበዛው ፡ እጃቸውን ፡ አልዘረጉም ።

፲፮ የቀሩትም ፡ በንጉሡ ፡ አገር ፡ ያሉ ፡ አይሁድ ፡ ተሰብስበው ፡ ለሕይወታቸው ፡ ቆሙ ፥ ከጠላቶቻቸውም ፡ ዐረፉ ፤ ከሚጠሉአቸውም ፡ ሰባ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ገደሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ብዝበዛው ፡ እጃቸውን ፡ አልዘረጉም ። ፲፯ አዳር ፡ በሚባለው ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ ሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ይህ ፡ ተደረገ ፤ በአሥራ ፡ አራተኛውም ፡ ቀን ፡ ዐረፉ ፥ የግብዣና ፡ የደስታም ፡ ቀን ፡ አደረጉ ። ፲፰ በሱሳ ፡ የነበሩት ፡ አይሁድ ፡ ግን ፡ በአሥራ ፡ ሦስተኛውና ፡ በአሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ ተሰበሰቡ ፤ በአሥራ ፡ አምስተኛውም ፡ ቀን ፡ ዐረፉ ፥ የመጠጥና ፡ የደስታም ፡ ቀን ፡ አደረጉት ። ፲፱ ስለዚህም ፡ በመንደሮችና ፡ ባልተመሸጉ ፡ ከተሞች ፡ የሚኖሩ ፡ አይሁድ ፡ አዳር ፡ በሚባለው ፡ ወር ፡ አሥራ ፡ አራተኛውን ፡ ቀን ፡ የደስታና ፡ የመጠጥ ፡ የመልካምም ፡ ቀን ፥ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ ስጦታ ፡ የሚሰጣጡበት ፡ ቀን ፡ ያደርጉታል ።

፳ መርዶክዮስም ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ጻፈ ፥ በንጉሡም ፡ በአርጤክስስ ፡ አገሮች ፡ ሁሉ ፡ በቅርብና ፡ በሩቅ ፡ ወዳሉት ፡ አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ ደብዳቤዎችን ፡ ላከ ። ፳፩ በየዓመቱም ፡ አዳር ፡ በሚባለው ፡ ወር ፡ አሥራ ፡ አራተኛውና ፡ አሥራ ፡ አምስተኛው ፡ ቀን ፥ ፳፪ አይሁድ ፡ ከጠላቶቻቸው ፡ ዕረፍትን ፡ ያገኙበት ፡ ቀን ፥ ወሩም ፡ ከኀዘን ፡ ወደ ፡ ደስታ ፡ ከልቅሶም ፡ ወደ ፡ መልካም ፡ ቀን ፡ የተለወጠበት ፡ ወር ፡ ሆኖ ፡ ይጠብቁት ፡ ዘንድ ፥ የግብዣና ፡ የደስታም ፡ ቀን ፥ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ ስጦታ ፡ የሚሰጣጡበትና ፡ ለድሆች ፡ ስጦታ ፡ የሚሰጡበት ፡ ቀን ፡ ያደርጉት ፡ ዘንድ ፡ አዘዛቸው ። ፳፫ አይሁድም ፡ ለመሥራት ፡

የጀመሩትን ÷ መርዶክዮስም ፡ የጻፈላቸውን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ተቀበሉት ፤ ፳፬ አጋጋዊው ፡ የሐመዳቱ ፡ ልጅ ፡ የአይሁድ ፡ ሁሉ ፡ ጠላት ፡ ሐማ ፡ አይሁድን ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ ተተንኵሎ ፡ ነበር ፤ ሊደመስሳቸውና ፡ ሊያጠፋቸውም ፡ ፉር ፡ የሚባል ፡ ዕጣ ፡ ጥሎ ፡ ነበር ። ፳፭ አስቴርም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ፊት ፡ በገባች ፡ ጊዜ ፡ በአይሁድ ፡ ላይ ፡ የተተነኰለው ፡ ክፉ ፡ ተንኰል ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ እንዲመለስ ÷ እርሱና ፡ ልጆቹም ፡ በግንድ ፡ ላይ ፡ እንዲሰቀሉ ፡ በደብዳቤው ፡ አዘዘ ።

፳፮ ስለዚህም ፡ እነዚህ ፡ ቀኖች ፡ እንደ ፡ ፉር ፡ ስም ፡ ፉሪም ፡ ተባሉ ። በዚህም ፡ ደብዳቤ ፡ ስለ ፡ ተጻፈው ፡ ቃል ፡ ሁሉ ÷ ስላዩትና ፡ ስላገ ፳፯፤፳፰ ኙአቸውም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ÷ አይሁድ ፡ እነዚህን ፡ ሁለት ፡ ቀኖች ፡ እንደ ፡ ጽሕፈቱና ፡ እንደ ፡ ጊዜው ፡ በየዓመቱ ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ÷ እነዚህም ፡ ቀኖች ፡ በየትውልዳቸውና ፡ በየወገናቸው ፡ በየአገራቸውም ፡ በየከተማቸውም ፡ የታሰቡና ፡ የተከበሩ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ÷ እነዚህም ፡ የፉሪም ፡ ቀኖች ፡ በአይሁድ ፡ ዘንድ ፡ እንዳይሻሩ ÷ መታሰባቸውም ፡ ከዘራቸው ፡ እንዳይቈረጥ ÷ በራሳቸውና ፡ በዘራቸው ፡ ወደ ፡ እነርሱም ፡ በተጠጉት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እንዳይቀር ፡ ሥርዓት ፡ አድርገው ፡ ተቀበሉ ።

፳፱ የአቢካኢልም ፡ ልጅ ፡ ንግሥቲቱ ፡ አስቴርና ፡ አይሁዳዊው ፡ መርዶክዮስ ፡ ይህችን ፡ ስለ ፡ ፉሪም ፡ የምትናገረውን ፡ ሁለተኛይቱን ፡ ደብዳቤ ፡ በሥልጣናቸው ፡ ሁሉ ፡ ያጸኑአት ፡ ዘንድ ፡ ጻፉ ። ፴ ደብዳቤዎቹንም ፡ በአርጤክስስ ፡ መንግሥት ፡ በመቶ ፡ ሀያ ፡ ሰባቱ ፡ አገሮች ፡ ወዳሉ ፡ አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ በሰላምና ፡ በእውነት ፡ ቃል ፡ ላኩ ። ፴፩ እነዚህንም ፡ የፉሪም ፡ ቀኖች ÷ አይሁዳዊው ፡ መርዶክዮስና ፡ ንግሥቲቱ ፡ አስቴር ፡ እንዳዘዙ ÷ ለራሳቸውና ፡ ለዘራቸውም ፡ የጾማቸውንና ፡ የልቅሶአቸውን ፡ ነገር ፡ ለማክበር ፡ እንደ ፡ ተቀበሉ ÷ በየጊዜያቸው ፡ ያጸኑ ፡ ዘንድ ፡ ጻፉ ። ፴፪ የአስቴርም ፡ ትእዛዝ ፡ ይህን ፡ የፉሪምን ፡ ነገር ፡ አጸና ፤ በመጽሐፍም ፡ ተጻፈ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ ንጉሡም ፡ አርጤክስስ ፡ በምድርና ፡ በባሕር ፡ ፪ ደሴቶች ፡ ላይ ፡ ግብር ፡ ጣለ ። የኃይሉና ፡ የብርታቱም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ንጉሡም ፡ እስከ ፡ ምን ፡ ድረስ ፡ እንዳከበረው ፡ የመርዶክዮስ ፡ ክብር ፡ ታላቅነት ÷ በሜዶንና ፡ በፋርስ ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? ፫ አይሁዳዊውም ፡ መርዶክዮስ ፡ ለንጉሡ ፡ ለአርጤክስስ ፡ በማዕርግ ፡ ሁለተኛ ፡ ነበረ ፤ በአይሁድም ፡ ዘንድ ፡ የከበረ ÷ በብዙ ፡ ወንድሞችም ፡ ዘንድ ፡ የተወደደ ÷ ለሕዝቡም ፡ መልካምን ፡ የፈለገ ÷ ለዘሩም ፡ ሁሉ ፡ በደኅና ፡ የተናገረ ፡ ነበረ ።

# መ ጽ ሐ ፈ ፡ ኢ ዮ ብ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ ዖፅ ፡ በሚባል ፡ አገር ፡ ስሙ ፡ ኢዮብ ፡ የተባለ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ያም ፡ ሰው ፡ ፍጹምና ፡ ቅን ÷ እግዚአብሔርንም ፡ የሚፈራ ÷ ፪ ከክፋትም ፡ የራቀ ፡ ነበረ ። ሰባትም ፡ ወንዶች ፡ ሦስትም ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ተወልደውለት ፡ ፫ ነበር ። ሀብቱም ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡ በጎች ÷ ሦስት ፡ ሺህም ፡ ግመሎች ÷ አምስት ፡ መቶም ፡ ጥማድ ፡ በሬ ÷ አምስት ፡ መቶም ፡ እንስት ፡ አህዮች ፡ ነበረ ÷ እጅግ ፡ ብዙም ፡ ባሪያዎች ፡ ነበሩት ፤ ያም ፡ ሰው ፡ በምሥራቅ ፡ ካሉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ፬ ይልቅ ፡ ታላቅ ፡ ነበረ ። ወንዶች ፡ ልጆቹም ፡ ሄደው ፡ በየተራ ፡ በያንዳንዳቸው ፡ ቤት ፡ ግብዣ ፡ ያደርጉ ፡ ነበር ፤ ሦስቱ ፡ እኅቶቻቸውም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ይበሉና ፡ ይጠጡ ፡ ዘንድ ፡ እነርሱ ፡ ልከው ፡ ይጠሩአቸው ፡ ነበር ። ፭ የግብዣውም ፡ ቀኖች ፡ ባለፉ ፡ ጊዜ ፡ ኢዮብ ፡— ምናልባት ፡ ልጆቼ ፡ በድለው ÷ እግዚአብሔርንም ፡ በልባቸው ፡ ሰድበው ፡ ይሆናል ፡ ብሎ ፡ ይልክና ፡ ይቀድሳቸው ፡ ነበር ፤ ኢዮብም ፡ ማልዶ ፡ ተነሣ ÷ እንደ ፡ ቍጥራቸውም ፡ ሁሉ ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረበ ። እንዲሁ ፡ ኢዮብ ፡ ሁልጊዜ ፡ ያደርግ ፡ ነበር ።

፮ ከዕለታት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ የአምላክ ፡ ልጆች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለመቆም ፡ መጡ ÷ ሰይጣንም ፡ ደግሞ ፡ በመካከላቸው ፡ መጣ ። ፯ እግዚአብሔርም ፡ ሰይጣንን ፡— ከወዴት ፡ መጣህ ? አለው ። ሰይጣንም ፡— ምድርን ፡ ሁሉ ፡ ዞርሁአት ÷ በእርስዋም ፡ ተመላለስሁ ፡ ብሎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መለሰ ። ፰ እግዚአብሔርም ፡ ሰይጣንን ፡— በውኑ ፡ ባሪያዬን ፡ ኢዮ

የጀመሩትን ÷ መርዶክዮስም፡ የጻፈላቸውን፡
፳፬፤ ያደርጉ፡ዘንድ፡ ተቀበሉት ፤ አጋጋዊው፡የሐ
መዳቱ፡ልጅ፡የአይሁድ፡ሁሉ፡ ጠላት፡ ሐማ፡
አይሁድን፡ያጠፉ፡ዘንድ፡ ተተንኰሎ፡ነበር፤
ሊደመስሳቸውና፡ሊያጠፋቸውም፡ፉር፡የሚ
፳፭፤ ባል፡ ዕጣ፡ ጥሎ፡ ነበር ። አስቴርም፡ ወደ፡
ንጉሡ፡ፊት፡በገባች፡ጊዜ፡ በአይሁድ፡ላይ፡
የተተነኰለው፡ ክፉ፡ ተንኰል፡ በራሱ፡ ላይ፡
እንዲመለስ ÷ እርሱና፡ ልጆቹም፡ በግንድ፡
ላይ፡እንዲሰቀሉ፡በደብዳቤው፡አዘዘ ።
፳፮፤ ስለዚህም፡ እነዚህ፡ ቀኖች፡ እንደ፡ ፉር፡
ስም፡ ፉሪም፡ ተባሉ ። በዚህም፡ ደብዳቤ፡
ስለ፡ተጻፈው፡ ቃል፡ሁሉ ÷ ስላዩትና፡ ስላገ
፳፯፤፳፰፤ ኙአቸውም፡ነገር፡ሁሉ ÷ አይሁድ፡እነዚህን፡
ሁለት፡ ቀኖች፡ እንደ፡ ጽሕፈቱና፡ እንደ፡
ጊዜው፡ በየዓመቱ፡ ይጠብቁ፡ ዘንድ ÷ እነዚ
ህም፡ ቀኖች፡ በየትውልዳቸውና፡ በየወገና
ቸው፡በየአገራቸውም፡በየከተማቸውም፡የታ
ሰቡና፡የተከበሩ፡ ይሆኑ፡ ዘንድ ÷ እነዚህም፡
የፉሪም፡ ቀኖች፡ በአይሁድ፡ ዘንድ፡ እንዳይ
ሻሩ ÷ መታሰቢቸውም፡ከዘራቸው፡እንዳይቈ
ረጥ ÷ በራሳቸውና፡ በዘራቸው፡ ወደ፡ እነር
ሱም፡ በተጠጉት፡ ሁሉ፡ ላይ፡ እንዳይቀር፡
ሥርዓት፡አድርገው፡ተቀበሉ ።
፳፱፤ የአቢካኢልም፡ልጅ፡ንግሥቲቱ፡አስቴርና፡
አይሁዳዊው፡ መርዶክዮስ፡ ይህችን፡ ስለ፡
ፉሪም፡የምትናገረውን፡ሁለተኛይቱን፡ደብ
ዳቤ፡በሥልጣናቸው፡ሁሉ፡ያጸኑአት፡ዘንድ፡
፴፤ ጻፉ ። ደብዳቤዎቹንም፡በአርጤክስስ፡መንግ
ሥት፡በመቶ፡ሀያ፡ሰባቱ፡አገሮች፡ ወዳሉ፡
አይሁድ፡ሁሉ፡በሰላምና፡በእውነት፡ ቃል፡
፴፩፤ ላኩ ። እነዚህንም፡ የፉሪም፡ ቀኖች ÷ አይሁ
ዳዊው፡ መርዶክዮስና፡ ንግሥቲቱ፡ አስቴር፡
እንዳዘዙ ÷ ለራሳቸውና፡ ለዘራቸውም፡ የጾማ
ቸውንና፡ የልቅሶአቸውን፡ ነገር፡ ለማክበር፡
እንደ፡ተቀበሉ ÷ በየጊዜያቸው፡ያጸኑ፡ዘንድ፡
፴፪፤ ጻፉ ። የአስቴርም፡ትእዛዝ፡ይህን፡የፉሪምን፡
ነገር፡አጸና፤ በመጽሐፍም፡ተጻፈ ።

## ምዕራፍ፡ ፲ ።

፩፤ ንጉሡም፡አርጤክስስ፡በምድርና፡በባሕር፡
፪፤ ደሴቶች፡ላይ፡ግብር፡ጣለ ። የኃይሉና፡የብ
ርታቱም፡ ሥራ፡ሁሉ፡ንጉሡም፡እስከ፡ምን፡
ድረስ፡ እንዳከበረው፡ የመርዶክዮስ፡ ክብር፡
ታላቅነት ÷ በሜዶንና፡ በፋርስ፡ ነገሥታት፡
፫፤ ታሪክ፡መጽሐፍ፡የተጻፈ፡አይደለምን ? አይ
ሁዳዊውም፡ መርዶክዮስ፡ ለንጉሡ፡ ለአርጤ
ክስስ፡በማዕርግ፡ሁለተኛ፡ነበረ፤በአይሁድም፡
ዘንድ፡የከበረ ÷ በብዙ፡ ወንድሞችም፡ ዘንድ፡
የተወደደ ÷ ለሕዝቡም፡ መልካምን፡ የፈለገ ÷
ለዘሩም፡ሁሉ፡በደኅና፡የተናገረ፡ነበረ ።

# መጽሐፈ፡ኢዮብ ።

## ምዕራፍ፡ ፩ ።

፩፤ ዖፅ፡ በሚባል፡ አገር፡ ስሙ፡ ኢዮብ፡ የተ
ባለ፡ አንድ፡ ሰው፡ ነበረ፤ ያም፡ ሰው፡ ፍጹ
ምና፡ ቅን ÷ እግዚአብሔርንም፡ የሚፈራ ÷
፪፤ ከክፋትም፡ የራቀ፡ ነበረ ። ሰባትም፡ ወንዶች፡
ሦስትም፡ ሴቶች፡ ልጆች፡ ተወልደውለት፡
፫፤ ነበር ። ሀብቱም፡ ሰባት፡ ሺህ፡ በጎች ÷ ሦስት፡
ሺህም፡ ግመሎች ÷ አምስት፡ መቶም፡ ጥማድ፡
በሬ ÷ አምስት፡ መቶም፡ እንስት፡ አህዮች፡
ነበረ ÷ እጅግ፡ ብዙም፡ ባሪያዎች፡ ነበሩት ፤
ያም፡ ሰው፡ በምሥራቅ፡ ካሉ፡ ሰዎች፡ ሁሉ፡
፬፤ ይልቅ፡ ታላቅ፡ ነበረ ። ወንዶች፡ ልጆቹም፡
ሄደው፡በየተራ፡በያንዳንዳቸው፡ቤት፡ግብዣ፡
ያደርጉ፡ነበር፤ ሦስቱ፡እኅቶቻቸውም፡ ከእነ
ርሱ፡ ጋር፡ ይበሉና፡ ይጠጡ፡ ዘንድ፡ እነ
ርሱ፡ ልከው፡ ይጠሩአቸው፡ ነበር ። የግብዣ
፭፤ ውም፡ ቀኖች፡ ባለፉ፡ ጊዜ፡ ኢዮብ ፡— ምና
ልባት፡ ልጆቼ፡ በድለው ÷ እግዚአብሔርንም፡
በልባቸው፡ ሰድበው፡ ይሆናል፡ ብሎ፡ ይል
ክና፡ ይቀድሳቸው፡ ነበር፤ ኢዮብም፡ ማልዶ፡
ተነሣ ÷ እንደ፡ ቍጥራቸውም፡ ሁሉ፡ የሚቃ
ጠል፡ መሥዋዕት፡ አቀረበ ። እንዲሁ፡ ኢዮብ፡
ሁልጊዜ፡ ያደርግ፡ ነበር ።
፮፤ ከዕለታት፡ አንድ፡ ቀን፡ እንዲህ፡ ሆነ፤ የእግዚአብሔርም
ላክ፡ ልጆች፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ለመቆም፡
መጡ ÷ ሰይጣንም፡ ደግሞ፡ በመካከላቸው፡
፯፤ መጣ ። እግዚአብሔርም፡ ሰይጣንን ፡— ከወ
ዴት፡ መጣህ? አለው ። ሰይጣንም ፡— ምድርን፡
ሁሉ፡ ዞርሁአት ÷ በእርስዋም፡ ተመላለስሁ፡
፰፤ ብሎ፡ ለእግዚአብሔር፡ መለሰ ። እግዚአብሔ
ርም፡ ሰይጣንን ፡— በውኑ፡ ባሪያዬን፡ ኢዮ

ብን ፡ ተመለከትኸውን? በምድር ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ፍጹምና ፡ ቅን ፥ እግዚአብሔርንም ፡ የሚፈራ ፥ ከክፋትም ፡ የራቀ ፡ ሰው ፡ የለም ፡ አለው ። ፱ ሰይጣንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ፦ በውኑ ፡ ኢዮብ ፡ እግዚአ ብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ በከንቱ ፡ ነውን? ፲ እርሱ ንና ፡ ቤቱን ፡ በዙሪያውም ፡ ያሉትን ፡ ሁሉ ፡ አላጠርህለትምን ? የእጁን ፡ ሥራ ፡ ባርከህለ ታል ፥ ከብቱም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በዝቶአል ። ፲፩ ነገር ፡ ግን ፡ እጅህን ፡ ዘርግተህ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ዳብስ ፤ ፲፪ በእውነት ፡ በፊትህ ፡ ይሰድብሃል ። እግ ዚአብሔርም ፡ ሰይጣንን ፦ እነሆ ፡ ለእርሱ ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ በእጅህ ፡ ነው ፥ ነገር ፡ ግን ፡ በእ ርሱ ፡ ላይ ፡ እጅህን ፡ አትዘርጋ ፡ አለው ። ሰይ ጣንም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ወጣ ።

፲፫ አንድ ፡ ቀንም ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ የኢዮብ ፡ ወን ዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ በታላቅ ፡ ወንድማቸው ፡ ቤት ፡ ይበሉና ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ይጠጡ ፡ ነበር ። ፲፬ መልክተኛም ፡ ወደ ፡ ኢዮብ ፡ መጥቶ ፦ በሬዎች ፡ እርሻ ፡ ያርሱ ፥ በአጠገባቸውም ፡ አህዮች ፡ ፲፭ ይሰማሩ ፡ ነበር ፤ የሳባም ፡ ሰዎች ፡ አደጋ ፡ ጣሉ ፥ ወሰዱአቸውም ፥ ብላቴኖቹንም ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ ገደሉ ፤ እኔም ፡ እነግርህ ፡ ዘንድ ፡ ብቻ ፲፮ ዬን ፡ አመለጥሁ ፡ አለው ። እርሱም ፡ ገና ፡ ሲና ገር ፡ ሌላ ፡ መጥቶ ፦ የእግዚአብሔር ፡ እሳት ፡ ከሰማይ ፡ ወደቀች ፥ በጎቹንም ፡ አቃጠለች ፥ ጠባቂዎችንም ፡ በላች ፤ እኔም ፡ እነግርህ ፡ ዘንድ ፡ ፲፯ ብቻዬን ፡ አመለጥሁ ፡ አለው ። እርሱም ፡ ገና ፡ ሲናገር ፡ ሌላ ፡ መጥቶ ፦ ከለዳውያን ፡ በሦ ስት ፡ ረድፍ ፡ ተከፍለው ፡ በግመሎች ፡ ላይ ፡ አደጋ ፡ ጣሉ ፥ ወሰዱአቸውም ፥ ብላቴኖቹ ንም ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ ገደሉ ፤ እኔም ፡ እነግርህ ፡ ፲፰ ዘንድ ፡ ብቻዬን ፡ አመለጥሁ ፡ አለው ። እር ሱም ፡ ገና ፡ ሲናገር ፡ ሌላ ፡ መጥቶ ፦ ወንዶ ችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆችህ ፡ በታላቅ ፡ ወንድማ ቸው ፡ ቤት ፡ ይበሉና ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ይጠጡ ፡ ፲፱ ነበር ፤ እነሆም ፥ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ከምድረ ፡ በዳ ፡ መጥቶ ፡ የቤቱን ፡ አራቱን ፡ ማዕዘን ፡ መታው ፥ በብላቴኖቹም ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፥ ሞቱም ፤ እኔም ፡ እነግርህ ፡ ዘንድ ፡ ብቻዬን ፡ አመለጥሁ ፡ አለው ። ፳ ኢዮብም ፡ ተነሣ ፡ መጐናጸፊያውንም ፡ ቀደደ ፥ ራሱንም ፡ ተላጨ ፥ በምድርም ፡ ላይ ፡ ተደ ፳፩ ፍቶ ፡ ሰገደ ፤ እንዲህም ፡ አለ ፦ ራቁቴን ፡ ከእ ናቴ ፡ ማኅፀን ፡ ወጥቻለሁ ፥ ራቁቴንም ፡ ወደዚያ ፡ እመለሳለሁ ፤ እግዚአብሔር ፡ ሰጠ ፥ እግዚአብ ሔርም ፡ ነሣ ፤ የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የተባረከ ፡ ፳፪ ይሁን ። በዚህ ፡ ሁሉ ፡ ኢዮብ ፡ አልበደለም ፥ ለእግዚአብሔርም ፡ ስንፍናን ፡ አልሰጠም ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ከዕለታት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ የእ ምላክ ፡ ልጆች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለመ ቆም ፡ መጡ ፥ ሰይጣን ፡ ደግሞ ፡ በእግዚአብ ሔር ፡ ፊት ፡ ለመቆም ፡ በመካከላቸው ፡ መጣ ። ፪ እግዚአብሔርም ፡ ሰይጣንን ፦ ከወዴት ፡ መጣህ? አለው ። ሰይጣንም ፦ በምድር ፡ ላይ ፡ ዞርሁ ፥ በእርስዋም ፡ ተመላለስሁ ፡ ብሎ ፡ ለእ ፫ ግዚአብሔር ፡ መለሰ ። እግዚአብሔርም ፡ ሰይ ጣንን ፦ በውኑ ፡ ባሪያዬን ፡ ኢዮብን ፡ ተመለ ከትኸውን ? በምድር ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ፍጹምና ፡ ቅን ፥ እግዚአብሔርንም ፡ የሚፈራ ፥ ከክፋትም ፡ የራቀ ፡ ሰው ፡ የለም ፤ በከንቱም ፡ አጠፋው ፡ ዘንድ ፡ አንተ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ምንም ፡ ብታንቀሳቅሰኝ ፥ እስከ ፡ አሁን ፡ ፍጹ ፬ ምነቱን ፡ ይዞአል ። ሰይጣንም ፡ መልሶ ፡ እግ ዚአብሔርን ፦ ቁርበት ፡ ስለ ፡ ቁርበት ፡ ነው ፤ ሰው ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ሕይወቱ ፡ ይሰጣል ። ፭ ነገር ፡ ግን ፡ አሁን ፡ እጅህን ፡ ዘርግተህ ፡ አጥን ቱንና ፡ ሥጋውን ፡ ዳብስ ፤ በእውነት ፡ በፊትህ ፡ ፮ ይሰድብሃል ፡ አለው ። እግዚአብሔርም ፡ ሰይ ጣንን ፦ ሕይወቱን ፡ ተወው ፡ እንጂ ፡ እነሆ ፥ እርሱ ፡ በእጅህ ፡ ነው ፡ አለው ።

፯ ሰይጣንም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ወጣ ፥ ኢዮብንም ፡ ከእግሩ ፡ ጫማ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ፰ አናቱ ፡ ድረስ ፡ በክፉ ፡ ቍስል ፡ መታው ። ሥጋ ውንም ፡ ይፍቅበት ፡ ዘንድ ፡ ገል ፡ ወሰደ ፥ በአ ፱ መድም ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ። ሚስቱም ፦ እስከ ፡ አሁን ፡ ፍጹምነትህን ፡ ይዘሃልን ? እግዚአ ብሔርን ፡ ስደብና ፡ሙት ፡ አለችው ።

(የሚቀጥለው ፡ ከግሪክ ፡ የተጨመረ ፡ ነው ።)

ዳግመኛ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጥቂት ፡ ወራት ፡ ደጅ ፡ እጠ ናዋለሁ ፤ ዳግመኛም ፡ መከራውን ፡ እታገሠዋለሁ ፡ የቀ ድሞ ፡ ኑሮዬንም ፡ ተስፋ ፡ አደርገዋለሁ ፡ ትላለህን? አለ ችው ። እንደዚህሳ ፡ እንዳትል ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ እነሆ ፡ ስም ፡ አጠራርህ ፡ ጠፋ ፤ ሴቶች ፡ ልጆቼና ፡ ወንዶች ፡ ልጆቼም ፡ሞቱ ፡ እኔስ ፡ ዘጠኝ ፡ ወር ፡ ሳረግዝ ፡ ሳምጥ ፡ ስወልድ ፡ ሳይረቡኝ ፡ ሳይጠቅሙኝ ፡ በከንቱ ፡ ደከምሁ ፡ አለች ። አንተም ፡ በመግል ፡ ተውጠህ ፡ በትል ፡ ተከብ በህ ፡ ትኖራለህ ፤ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ ስትዛብር ፡ ታድራ ለህ ። እኔ ፡ ግን ፡ እየዞርሁ ፡ እቀላውጣለሁ ። ከአንዱ ፡ አገር ፡ ወደ ፡ አንዱ ፡ አገር ፡ ከአንዱ ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ አ ንዱ ፡ ቤት ፡ እሄዳለሁ ፤ ከድካሜ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ካለ ፡ ከችግሬም ፡ አርፍ ፡ ዘንድ ፡ ከጧት ፡ ጀምሮ ፡ ፀሐይ ፡ እስኪገባ ፡ ድረስ ፡ እጠብቃለሁ ፤ አሁን ፡ ግን ፡ እግዚ አብሔርን ፡ የማይገባ ፡ ቃል ፡ ተናግረሽው ፡ ሙት ፡ አለች ።

፲ እርሱ ፡ ግን ፦ አንቺ ፡ ከሰነፎች ፡ ሴቶች ፡ እንደ ፡ አንዲቱ ፡ ተና ገርሽ ፤ ከእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ መልካሙን ፡ ተቀበልን ፥ ክፉ ፡ ነገርንስ ፡ አንቀበልምን ? አላት ። በዚህ ፡ ሁሉ ፡ ኢዮብ ፡ በከንፈሩ ፡ አል በደለም ።

፲፩ ሦስቱም ፡ የኢዮብ ፡ ወዳጆች ፡ ይህን ፡ የደረ ሰበትን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ሰምተው ፡ ከየአገ ራቸው ፡ መጡ ፤ እነርሱም ፡ ቴማናዊው ፡ ኤል ፋዝ ፥ ሹሐዊው ፡ በልዳዶስ ፥ ነዕማታዊው ፡ ሶፋር ፡ ነበሩ ። እነርሱም ፡ ሊያዝኑለትና ፡ ሊያ ጽናኑት ፡ በአንድነት ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ለመምጣት ፡

፲፪ ተስማሙ ። ከሩቅም ፡ ሆነው ፡ ዓይናቸውን ፡ በነሡ ፡ ጊዜ ፡ አላወቁትም ፤ ድምፃቸውንም ፡ አሰምተው ፡ አለቀሱ ፤ እያንዳንዳቸውም ፡ መጐናጸፊያቸውን ፡ ቀደዱ ፥ ወደ ፡ ላይም ፡ ወደ ፡ ራሳቸው ፡ ላይ ፡ ትቢያ ፡ ነሰነሱ ።
፲፫ ሰባት ፡ ቀንና ፡ ሰባት ፡ ሌሊትም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ተቀመጡ ፤ ሕመሙም ፡ እጅግ ፡ እንደ ፡ በዛ ፡ አይተዋልና ፡ ከእነርሱ ፡ አንድ ፡ ቃል ፡ የሚናገረው ፡ አልነበረም ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ኢዮብ ፡ አፉን ፡ ከፍቶ ፡ የተወለደበትን ፡ ቀን ፡ ረገመ ።
፪ ኢዮብም ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦
፫ ያ ፡ የተወለድሁበት ፡ ቀን ፡ ይጥፋ ፥
ያም ፦ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ተፀነሰ ፡ የተባለበት ፡ ሌሊት ።
፬ ያ ፡ ቀን ፡ ጨለማ ፡ ይሁን ፤
እግዚአብሔር ፡ ከላይ ፡ አይመልከተው ፥
ብርሃንም ፡ አይብራበት ።
፭ ጨለማና ፡ የሞት ፡ ጥላ ፡ የራሳቸው ፡ ገንዘብ ፡ ያድርጉት ፤
ዳመናም ፡ ይረፍበት ፤
የቀን ፡ ጨለማ ፡ ሁሉ ፡ ያስፈራው ።
፮ ያን ፡ ሌሊት ፡ ጨለማ ፡ ይያዘው ፤
በዓመቱ ፡ ቀኖች ፡ መካከል ፡ ደስ ፡ አይበለው ፤
በወሮች ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፡ አይቈጠር ።
፯ እነሆ ፥ ያ ፡ ሌሊት ፡ መካን ፡ ይሁን ፤
እልልታ ፡ አይግባበት ።
፰ ሌዋታንን ፡ ለማንቀሳቀስ ፡ የተዘጋጁ ፡
ቀኑን ፡ የሚረግሙ ፡ ይርገሙት ።
፱ አጥቢያ ፡ ኮከቦች ፡ ይጨልሙ ፤
ብርሃንን ፡ ቢጠባበቅ ፡ አያግኘው ፥
የንጋትንም ፡ ቅንድብ ፡ አይይ ፤
፲ የእናቴን ፡ ማኅፀን ፡ ደጅ ፡ አልዘጋምና ፥
መከራንም ፡ ከዓይኔ ፡ አልሰወረምና ።
፲፩ በማኅፀን ፡ ሳለሁ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አልሞትሁም ?
ከሆድስ ፡ በወጣሁ ፡ ጊዜ ፡ ፈጥኜ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አልጠፋሁም ?
፲፪ ጕልበቶች ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ተቀበሉኝ ?
ጡትስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ጠባሁ ?
፲፫ አሁን ፡ ተኝቼ ፡ ዝም ፡ ባልሁ ፡ ነበር ፤
አንቀላፍቼ ፡ በረፍሁ ፡ ነበር ፤
፲፬ የፈረሰውን ፡ ለራሳቸው ፡ ከሚሠሩት ፡
ከምድር ፡ ነገሥታትና ፡ መካሮች ፡ ጋር ፥
፲፭ ወይም ፡ ቤታቸውን ፡ ብር ፡ ከሞሉ ፡
ወርቅም ፡ ከላቸው ፡ መኳንንት ፡ ጋር ፥
፲፮ ወይም ፡ እንደ ፡ ተቀበረ ፡ ጭንጋፍ ፥
ብርሃንም ፡ እንዳላዩ ፡ ሕፃናት ፡ በሆንሁ ፡ ነበር ።
፲፯ ክፉዎች ፡ በዚያ ፡ መናደዳቸውን ፡ ይተዋሉ ፤
በዚያም ፡ ደካሞች ፡ ያርፋሉ ።
፲፰ በዚያ ፡ ግዞተኞች ፡ በአንድነት ፡ ተዘልለው ፡ ተቀምጠዋል ፤
የአስጨናቂውን ፡ ድምፅ ፡ አይሰሙም ።
፲፱ ታናሽና ፡ ታላቅ ፡ በዚያ ፡ አሉ ፤
ባሪያም ፡ ከጌታው ፡ ነጻ ፡ ወጥቶአል ።

፳ በመከራ ፡ ላሉት ፡ ብርሃን ፥
ነፍሳቸው ፡ መራራ ፡ ለሆነችባቸው ፥
፳፩ የተሰወረ ፡ ሀብትን ፡ ከሚቈፍሩ ፡ ይልቅ ፡
ሞትን ፡ ለሚጠብቁ ፡ ለማያገኙትም ፥
፳፪ መቃብርን ፡ ባገኙ ፡ ጊዜ ፡
በእልልታ ፡ ደስ ፡ ለሚላቸው ፥ ሐሤትንም ፡ ለሚያደርጉ ፡
ሕይወት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ተሰጠ ?
፳፫ መንገዱ ፡ ለተሰወረበት ፡ ሰው ፥
እግዚአብሔርም ፡ በአጥር ፡ ላጠረው ፡
ብርሃን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ተሰጠ ?
፳፬ ከእንጀራዬ ፡ በፊት ፡ ልቅሶዬ ፡ መጥቶአልና ፥
ጩኸቴም ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ ፈስሶአል ።
፳፭ የፈራሁት ፡ ነገር ፡ መጥቶብኛልና ፥
የደነገጥሁበትም ፡ ደርሶብኛል ።
፳፮ ተዘልዬ ፡ አልተቀመጥሁም ፥ አልተማመንሁም ፥ አላረፍሁም ፤
ነገር ፡ ግን ፡ መከራ ፡ መጣብኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ቴማናዊውም ፡ ኤልፋዝ ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦
፪ አንድ ፡ ሰው ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይናገር ፡ ዘንድ ፡ ቢሞክር ፡ ትቀየማለህን ?
ቃልንስ ፡ ከመናገር ፡ ሊቀር ፡ የሚችል ፡ ማን ፡ ነው ?
፫ እነሆ ፥ አንተ ፡ ብዙዎችን ፡ ታስተምር ፡ ነበር ፥
የደከሙትንም ፡ እጆች ፡ ታበረታ ፡ ነበር ፥
፬ ቃልህ ፡ የሚሰናከለውን ፡ ያስነሣ ፡ ነበር ፥
አንተም ፡ የሚብረከረከውን ፡ ጕልበት ፡ ታጸና ፡ ነበር ።
፭ አሁን ፡ ግን ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ መጥቶአል ፥ አንተም ፡ ደከምህ ፤
ደርሶብሃል ፥ አንተም ፡ ተቸገርህ ።
፮ አምላክህን ፡ መፍራትህ ፡ መጽናናትህ ፥
የቅንነትህም ፡ መንገድ ፡ ተስፋህ ፡ አይደለምን ?
፯ እባክህ ፡ አስብ ፥ ንጹሕ ፡ ሆኖ ፡ የጠፋ ፡ ማን ፡ ነው ?
ከልበ ፡ ቅንስ ፡ የተደመሰሰ ፡ ማን ፡ ነው ?
፰ እኔ ፡ እንዳየሁ ፥ ኃጢአትን ፡ የሚያርሱ ፥
መከራንም ፡ የሚዘሩ ፡ ይህንኑ ፡ ያጭዳሉ ።
፱ በእግዚአብሔር ፡ እስትንፋስ ፡ ይጠፋሉ ፥
በቍጣውም ፡ መንፈስ ፡ ያልቃሉ ።
፲ የአንበሳ ፡ ጩኸት ፥ የጨካኝ ፡ አንበሳ ፡ ድምፅ ፥
የአንበሳ ፡ ደቦል ፡ ጥርስ ፡ ተሰበረ ።
፲፩ አሮጌ ፡ አንበሳ ፡ አደን ፡ በማጣት ፡ ይሞታል ፥
የአንበሳይቱም ፡ ግልገሎች ፡ ይበተናሉ ።

፲፪ ለእኔም ፡ በምሥጢር ፡ ቃል ፡ መጣልኝ ፥
ጆሮዬም ፡ ሹክሹክታውን ፡ ሰማች ።
፲፫ በሌሊት ፡ ሕልም ፡ አሳብ ፡ ሲነሣ ፥

የከበደም ፡ እንቅልፍ ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ሲወድቅ ፥
፲፬ ፡ አጥንቴን ፡ ሁሉ ፡ ያናወጡ ፡
ድንጋጤና ፡ መንቀጥቀጥ ፡ ወደቁብኝ ።
፲፭ ፡ መንፈስም ፡ በፊቴ ፡ አለፈ ፤
የሥጋዬ ፡ ጠጕር ፡ ቆመ ።
፲፮ ፡ እርሱም ፡ ቆመ ፥ መልኩን ፡ ግን ፡ ለመለየት ፡ አልቻልሁም ፥
ምሳሌም ፡ በዓይኔ ፡ ፊት ፡ ነበረ ፤
የዝምታ ፡ ድምፅ ፡ ሰማሁ ፡—
፲፯ ፡ በውኑ ፡ ሰው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ጻድቅ ፡ ሊሆን ፥
ወይስ ፡ ሰው ፡ በፈጣሪው ፡ ፊት ፡ ሊነጻ ፡ ይችላልን ?
፲፰ ፡ እነሆ ፥ በባሪያዎቹ ፡ አይታመንም ፤
መላእክቱንም ፡ ስንፍና ፡ ይከስሳቸዋል ፤
፲፱ ፡ ይልቁንስ ፡ በጭቃ ፡ ቤት ፡ የሚኖሩ ፥
መሠረታቸው ፡ በትቢያ ፡ ውስጥ ፡ የሆነ ፥
ከብል ፡ በፊት ፡ የሚጨፈለቁ ፡ እንዴት ፡ ይሆኑ ?
፳ ፡ በጥዋትና ፡ በማታ ፡ መካከል ፡ ይሰባበራሉ ፤
ማንም ፡ ሳያስብ ፡ ለዘላለም ፡ ይጠፋሉ ።
፳፩ ፡ ገመዳቸው ፡ የተነቀለ ፡ አይደለምን ?
አለጥበብም ፡ ይሞታሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ፡ አሁንም ፡ ጥራ ፤ የሚመልስልህ ፡ አለን ?
ከቅዱሳንስ ፡ ወደ ፡ ማናቸው ፡ ትዞራለህ ?
፪ ፡ ሰነፉን ፡ ሰው ፡ ቍጣ ፡ ይገድለዋል ፥
ሰነፉንም ፡ ቅንዓት ፡ ያጠፋዋል ።
፫ ፡ ሰነፍ ፡ ሰው ፡ ሥር ፡ ሰድዶ ፡ አየሁት ፥
ድንገትም ፡ መኖሪያውን ፡ ረገምሁ ።
፬ ፡ ልጆቹም ፡ ከደኅንነት ፡ ርቀዋል ፥
በበርም ፡ ውስጥ ፡ ተረግጠዋል ፥
የሚታደጋቸውም ፡ የለም ።
፭ ፡ የሰበሰበውንም ፡ ራብተኛ ፡ ይበላዋል ፥
ከእሾህም ፡ ውስጥ ፡ እንኳ ፡ ያወጣዋል ፤
የተጠማ ፡ ሀብታቸውን ፡ ዋጠ ።
፮ ፡ ችግር ፡ ከትቢያ ፡ አይመጣም ፥
መከራም ፡ ከመሬት ፡ አይበቅልም ፤
፯ ፡ የእሞራ ፡ ግልገሎች ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ እየበረሩ ፡ ከፍ ፡ እንዲሉ ፥
ሰው ፡ እንዲሁ ፡ ለመከራ ፡ ተወልዶአል ።

፰ ፡ እኔ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እለምን ፡ ነበር ፥
ነገሬንም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አቀርብ ፡ ነበር ።
፱ ፡ የማይመረመረውን ፡ ታላቅ ፡ ነገርና ፡
የማይቈጠረውን ፡ ተአምራት ፡ ያደርጋል ።
፲ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ዝናብን ፡ ይሰጣል ፥
በእርሻም ፡ ላይ ፡ ውኃ ፡ ይልካል ።
፲፩ ፡ የተዋረዱትን ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ያወጣል ፥
ኀዘንተኞችንም ፡ ለደኅንነት ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋቸዋል ።
፲፪ ፡ እጃቸውም ፡ ምክራቸውን ፡ እንዳይፈጽም ፡
የተንኰለኞችን ፡ አሳብ ፡ ከንቱ ፡ ያደርገዋል ።
፲፫ ፡ ጠቢባንን ፡ በተንኰላቸው ፡ ይይዛቸዋል ፤
የጠማሞችንም ፡ ምክር ፡ ይዘረዝራል ።
፲፬ ፡ በቀን ፡ ጨለማን ፡ ያገኛሉ ፥
በቀትርም ፡ ጊዜ ፡ በሌሊት ፡ እንዳሉ ፡ ይርመሰመሳሉ ።
፲፭ ፡ ድሀውንም ፡ ከአፋቸው ፡ ሰይፍ ፡
ከኃያሉም ፡ እጅ ፡ ያድነዋል ።
፲፮ ፡ ለምስኪኑም ፡ ተስፋ ፡ አለው ፤
ክፋት ፡ ግን ፡ አፍዋን ፡ ትዘጋለች ።

፲፯ ፡ እነሆ ፥ እግዚአብሔር ፡ የሚገሥጸው ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ፤
ስለዚህ ፡ ሁሉን ፡ የሚችለውን ፡ የአምላክን ፡ ተግሣጽ ፡ አትናቅ ።
፲፰ ፡ እርሱ ፡ ይሰብራል ፥ ይጠግንማል ፤
ያቈስላል ፥ እጆቹም ፡ ይፈውሳሉ ።
፲፱ ፡ በስድስት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ውስጥ ፡ ያድንሃል ፥
በሰባትም ፡ ውስጥ ፡ ክፋት ፡ አትነካህም ።
፳ ፡ በራብ ፡ ጊዜ ፡ ከሞት ፥
በሰልፍም ፡ ከሰይፍ ፡ እጅ ፡ ያድንሃል ።
፳፩ ፡ ከምላስ ፡ ጅራፍ ፡ ትሰወራለህ ፤
ጥፋትም ፡ ሲመጣ ፡ አትፈራም ።
፳፪ ፡ በጥፋትና ፡ በራብ ፡ ላይ ፡ ትስቃለህ ፤
ከምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊትም ፡ አትፈራም ፤
፳፫ ፡ ቃል ፡ ኪዳንህ ፡ ከምድረ ፡ በዳ ፡ ድንጋይ ፡ ጋር ፡ ይሆናልና ፤
የምድረ ፡ በዳም ፡ አራዊት ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይስማማሉና ።
፳፬ ፡ ድንኳንህም ፡ በሰላም ፡ እንዲሆን ፡ ታውቃለህ ፤
በረትህን ፡ ትጐበኛለህ ፡ አንዳችም ፡ አይጐድልብህም ።
፳፭ ፡ ዘርህም ፡ ታላቅ ፡ እንዲሆን ፥
ትውልድህም ፡ እንደ ፡ ምድር ፡ ሣር ፡ እንዲሆን ፡ ታውቃለህ ።
፳፮ ፡ በወራቱ ፡ የእህሉ ፡ ነዶ ፡ ወደ ፡ አውድማ ፡ እንዲገባ ፥
በረጅም ፡ ዕድሜ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ትገባለህ ።
፳፯ ፡ እነሆ ፥ ይህችን ፡ መረመርን ፥ የሰማነውም ፡ ይህ ፡ ነው ፤
አንተ ፡ ግን ፡ አንዳች ፡ ሠርተህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለራስህ ፡ እወቀው ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ፡ ኢዮብም ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—
፪ ፡ ትካዜዬ ፡ ምነው ፡ በተመዘነ ፡ ኖሮ !
መከራዬም ፡ ሁሉ ፡ ምነው ፡ በሚዛን ፡ ላይ ፡ በተደረገ ፡ ኖሮ !
፫ ፡ ከባሕር ፡ አሸዋ ፡ ይልቅ ፡ ይከብድ ፡ ነበርና ፤
ስለዚህ ፡ ቃሌ ፡ ደፋር ፡ ሆኖአል ።
፬ ፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ የአምላክ ፡ ፍላጻ ፡ በሥጋዬ ፡ ውስጥ ፡ ነው ፥
መርዙንም ፡ ነፍሴ ፡ ትጠጣለች ፤
የእግዚአብሔር ፡ ድንጋጤ ፡ በላዬ ፡ ተሰልፎአል ።
፭ ፡ በውኑ ፡ የሜዳ ፡ አህያ ፡ ሣር ፡ ሳለው ፡ ይጮኻልን ?
ወይስ ፡ በሬ ፡ ገለባ ፡ ሳለው ፡ ይጮኻልን ?

፮ የማይጣፍጥስ ፡ ነገር ፡ ያለ ፡ ጨው ፡ ይበላልን ?
ወይስ ፡ የእንቍላል ፡ ውኃ ፡ ይጥማልን ?
፯ ሰውነቴ ፡ ትነካው ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ አለችው ፤
እንደሚያስጸይፍ ፡ መብል ፡ ሆነብኝ ።

፰ ልመናዬ ፡ ምነው ፡ በደረሰልኝ !
እግዚአብሔርም ፡ ምኞቴን ፡ ምነው ፡ በሰጠኝ !
፱ እግዚአብሔርም ፡ ያደቀኝ ፡ ዘንድ ፡
እጁንም ፡ ለቅቆ ፡ ያጠፋኝ ፡ ዘንድ ፡ ወድዶ ፡
ቢሆን ፡ ኖሮ !
፲ መጽናናት ፡ በሆነልኝ ፡ ነበር ፤
በማይራራ ፡ ሕመም ፡ ሐሤት ፡ ባደረግሁ ፡ ነበር ÷
የቅዱሱን ፡ ቃል ፡ አልካድሁምና ።
፲፩ እጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ጕልበቴ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
እታገሥም ፡ ዘንድ ፡ ፍጻሜዬ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
፲፪ ጕልበቴ ፡ የድንጋይ ፡ ጕልበት ፡ ነውን ?
ሥጋዬስ ፡ እንደ ፡ ናስ ፡ ነውን ?
፲፫ በውኑ ፡ ረድኤት ፡ በእኔ ፡ እንደሌለ ፡
ጥበብም ፡ ሁሉ ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተበረረ ፡
አይደለምን ?

፲፬ ሁሉን ፡ የሚችለውን ፡ የአምላክን ፡ መፍራት ፡
ለሚተው ÷ ለመዘል ፡ ለቀረበው ፡ ስንኳ ፡
ወዳጁ ፡ ቸርነትን ፡ ሊያሳይ ፡ ይገባል ።
፲፭ ወንድሞቼ ፡ እንደ ፡ ፈፋ ÷
እንደሚያልፍ ፡ ፈፋ ፡ ሐሰተኞች ፡ ሆኑብኝ ።
፲፮ ከበረዶ ፡ የተነሣ ፡ ደፈረሱ ÷
አመዳይም ፡ ተሰወረባቸው ፤
፲፯ ፀሐይ ፡ በተኰሰች ፡ ጊዜ ፡ ይደርቃሉ ፤
በሙቀትም ፡ ጊዜ ፡ ከስፍራቸው ፡ ይጠፋሉ ።
፲፰ በየዳርቻቸውም ፡ የሚሄዱ ፡ ነጋዴዎች ፡ ፈቀቅ ፡
ይላሉ ፤
ወደ ፡ በረሃ ፡ ወጥተው ፡ ይጠፋሉ ።
፲፱ የቴማን ፡ ነጋዴዎች ፡ ተመለከቱ ÷
የሳባ ፡ መንገደኞችም ፡ ተጠባበቁአቸው ።
፳ ተስፋ ፡ አድርገዋቸው ፡ ነበርና ፡ አፈሩ ፤
ወደዚያ ፡ ደረሱ ÷ እፍረትም ፡ ያዛቸው ።
፳፩ አሁንም ፡ እናንተ ፡ እንደዚሁ ፡ ሆናችኋል ፤
መከራዬን ፡ አይታችሁ ፡ ፈራችሁ ።
፳፪ በውኑ ፡— እንዳች ፡ ነገር ፡ አምጡልኝ ፤
ወይስ ፡— ከብልጥግናችሁ ፡ ስጦታ ፡ አቅር
ቡልኝ ፤
፳፫ ወይስ ፡— ከጠላቴ ፡ እጅ ፡ አስጥሉኝ ፤
ወይስ ፡— ከአስጨናቂው ፡ እጅ ፡ አድኑኝ ፡ አል
ኋችሁን ?

፳፬ አስተምሩኝ ÷ እኔም ፡ ዝም ፡ እላለሁ ፤
የተሳሳትሁትንም ፡ ንገሩኝ ።
፳፭ የቅንነት ፡ ቃል ፡ እንዴት ፡ ኃይለኛ ፡ ነው !
የእናንተ ፡ ሙግት ፡ ግን ፡ ምን ፡ ይገሥጻል ?
፳፮ ተስፋ ፡ የሌለው ፡ ሰው ፡ ንግግር ፡ እንደ ፡ ነፋስ ፡
ነውና ፡
ቃሌን ፡ ትገሥጹ ፡ ዘንድ ፡ ታስባላችሁን ?
፳፯ በድሀ ፡ አደጉ ፡ ላይ ፡ ዕጣ ፡ ትጣጣላላችሁ ፤
ለወዳጃችሁም ፡ ጕድጓድ ፡ ትቈፍራላችሁ ።
፳፰ አሁንም ÷ እባካችሁ ÷ ወደ ፡ እኔ ፡ ተመልከቱ ፤
በፊታችሁም ፡ ሐሰት ፡ አልናገርም ።
፳፱ እባካችሁ ÷ ተመለሱ ፤ በደል ፡ አይሁን ፤
ጽድቄ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ነውና ፡ እንደ ፡ ጊዜ ፡
ተመለሱ ።
፴ በውኑ ፡ በአንደበቴ ፡ በደል ፡ ይገኛልን ?
አፌስ ፡ ተንኰልን ፡ ይለይ ፡ ዘንድ ፡ አይችል
ምን ?

ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ በምድር ፡ ላይ ፡ የሰው ፡ ሕይወት ፡ ብርቱ ፡
ሰልፍ ፡ አይደለምን ?
ወራቱም ፡ እንደ ፡ ምንደኛ ፡ ወራት ፡ አይደለ
ምን ?
፪ አገልጋይ ፡ ጥላ ፡ እንደሚመኝ ÷
ምንደኛም ፡ ደመወዙን ፡ እንደሚጠብቅ ÷
፫ እንዲሁ ፡ ዕጣዬ ፡ የከንቱ ፡ ወራት ፡ ሆነብኝ ÷
የድካምም ፡ ሌሊት ፡ ተወሰነችልኝ ።
፬ በተኛሁ ፡ ጊዜ ፡— መቼ ፡ እነሣለሁ ? እላለሁ ።
ሌሊቱ ፡ ግን ፡ ይረዝማል ÷
እስኪነጋ ፡ ድረስም ፡ እገለባበጣለሁ ።
፭ ሥጋዬ ፡ ትልና ፡ ጓል ፡ ለብሶአል ፤
ቁርበቴ ፡ ያፈከፍካል ፡ እንደ ፡ ገናም ፡ ይመግላል ።
፮ ዘመኔ ፡ ከሸማኔ ፡ መወርወርያ ፡ ይልቅ ፡ ይቸኩ
ላል ÷
ያለ ፡ ተስፋም ፡ ያልቃል ።
፯ ሕይወቴ ፡ እስትንፋስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስብ ፤
ዓይኔ ፡ መልካም ፡ ነገርን ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
አያይም ።
፰ የሚያየኝ ፡ ሰው ፡ ዓይን ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
አያየኝም ፤
ዓይንህ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ÷ እኔም ፡ አል
ገኝም ።
፱ ደመና ፡ ተበትኖ ፡ እንደሚጠፋ ÷
እንዲሁ ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ የሚወርድ ፡ ዳግመኛ ፡
አይወጣም ።
፲ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ዳግመኛ ፡ አይመለስም ÷
ስፍራውም ፡ ዳግመኛ ፡ አያውቀውም ።

፲፩ ስለዚህም ፡ አፌን ፡ አልከለክልም ፤
በመንፈሴ ፡ ጭንቀትን ፡ እናገራለሁ ፤
በነፍሴ ፡ ምሬት ፡ በኀዘን ፡ እንጐራጐራለሁ ።
፲፪ ጠባቂ ፡ ታስነሣብኝ ፡ ዘንድ ÷
እኔ ፡ ባሕር ፡ ወይስ ፡ አንበሪ ፡ ነኝን ?
፲፫ እኔም ፡— አልጋዬ ፡ ያጽናናኛል ÷
መኝታዬም ፡ የኀዘን ፡ እንጕርጕሮዬን ፡ ያቀል
ልኛል ፡ ባልሁ ፡ ጊዜ ÷
፲፬ አንተ ፡ በሕልም ፡ ታስፈራራኛለህ ÷
በራእይም ፡ ታስደነግጠኛለህ ፤
፲፭ ነፍሴም ፡ ከአጥንቴ ፡ ይልቅ ፡
መታነቅንና ፡ ሞትን ፡ መረጠች ።
፲፮ ሕይወቴን ፡ ናቅኋት ፤ ለዘላለም ፡ ልኖር ፡ አልወ
ድድም ፤

የሕይወቴ፡ዘመን፡እስትንፋስ፡ነውና፡ተወኝ።
፲፯፡ ሰው፡ምንድር፡ነው፡ታከብረው፡ዘንድ÷
ልብህንስ፡ትጥልበት፡ዘንድ÷
፲፰፡ ማለዳ፡ማለዳስ፡ትጐበኘው፡ዘንድ÷
ሁልጊዜስ፡ትፈታተነው፡ዘንድ?
፲፱፡ የማትተወኝ፡እስከ፡መቼ፡ነው?
ምራቄንስ፡እስክውጥ፡ድረስ፡የማትለቀቀኝ፡እስከ፡መቼ፡ነው?
፳፡ ሰውን፡የምትጠብቅ፡ሆይ÷በድዬስ፡እንደ፡ሆን፡ምን፡ላድርግልህ?
ስለ፡ምን፡እኔን፡ለአንተ፡ዓላማ፡አደረግኸኝ?
ስለ፡ምን፡እኔ፡ሸክም፡ሆንሁብህ?
፳፩፡ ስለ፡ምን፡መተላለፌን፡ይቅር፡አትልም?
ኃጢአቴንስ፡ስለ፡ምን፡አታስወግድልኝም?
አሁን፡በምድር፡ውስጥ፡እተኛለሁ፤
ማለዳ፡ትፈልገኛለህ÷አታገኘኝም።

## ምዕራፍ፡፰።

፩፡ ሹሐዊውም፡በልዳዶስ፡መለሰ፡እንዲህም፡አለ፤—
፪፡ እስከ፡መቼ፡ይህን፡ትናገራለህ?
የአፍህስ፡ቃል፡እስከ፡መቼ፡እንደ፡ዐውሎ፡ነፋስ፡ይሆናል?
፫፡ በውኑ፡እግዚአብሔር፡ፍርድን፡ያጣምማልን?
ሁሉንም፡የሚችል፡አምላክ፡ጽድቅን፡ያጣምማልን?
፬፡ ልጆችህ፡በድለውት፡እንደ፡ሆነ÷
እርሱ፡በበደላቸው፡እጅ፡ጥሎአቸዋል።
፭፡ እግዚአብሔርን፡ብትገሠግሥ÷
ሁሉንም፡የሚችለውን፡አምላክ፡ብትለምን÷
፮፡ ንጹሕና፡ቅን፡ብትሆን÷
በእውነት፡አሁን፡ስለ፡አንተ፡ይነቃል÷
የጽድቅህንም፡መኖሪያ፡ያከናውንልሃል።
፯፡ ጅማሬህም፡ታናሽ፡ቢሆንም፡እንኳ፡ፍጻሜህ፡እጅግ፡ይበዛል።
፰፡፱፡ ዘመናችን፡በምድር፡ላይ፡እንደ፡ጥላ፡ነውና፡እኛ፡የትናንት፡ብቻ፡ነን፤ምንም፡አናውቅም፤
ስለዚህ፡የቀደመውን፡ትውልድ፡ጠይቅ÷
አባቶቻቸውም፡ለመረመሩት፡ነገር፡ትጋ፤
፲፡ እነርሱ፡የሚያስተምሩህና፡የሚነግሩህ÷
ቃልንም፡ከልባቸው፡የሚያወጡ፡አይደሉምን?
፲፩፡ በውኑ፡ደንገል፡ረግረግ፡በሌለበት፡መሬት፡ይበቅላልን?
ወይስ፡ቄጠማ፡ውኃ፡በሌለበት፡በታ፡ይለመልማልን?
፲፪፡ ገና፡ሲለመልም፡ሳይቈረጥም÷
ከአትክልት፡ሁሉ፡በፊት፡ይደርቃል።
፲፫፡ እግዚአብሔርን፡የሚረሱ፡ሁሉ፡ፍጻሜአቸው፡እንዲሁ፡ነው፤
የዝንጉም፡ሰው፡ተስፋ፡ይጠፋል።
፲፬፡ ተስፋው፡ይቈረጣል÷
እምነቱም፡እንደ፡ሸረሪት፡ቤት፡ይሆናል።
፲፭፡ ቤቱን፡ይደገፈዋል÷አይቆምለትም፤
ይይዘውማል÷አይጸናለትም።
፲፮፡ ፀሐይም፡ሳይተኵስ፡ይለመልማል÷
ጫፉም፡በአታክልቱ፡በታ፡ይወጣል።
፲፯፡ በድንጋይ፡ክምር፡ላይ፡ሥሩ፡ይጠመጠማል፤
የድንጋዮቹን፡በታ፡ይመለከታል።
፲፰፡ ከበታው፡ቢጠፋ፡—
አላየሁህም፡ብሎ፡ይክደዋል።
፲፱፡ እነሆ÷የመንገዱ፡ደስታ፡እንዲህ፡ነው፤
ሌሎችም፡ከመሬት፡ይበቅላሉ።
፳፡ እነሆ÷እግዚአብሔር፡ፍጹሙን፡ሰው፡አይጥለውም÷
የኃጢአተኞችንም፡እጅ፡አያበረታም።
፳፩፡ አፍህን፡እንደ፡ገና፡ሳቅ፡ይሞላል÷
ከንፈሮችህንም፡እልልታ፡ይሞላል።
፳፪፡ የሚጠሉህ፡እፍረት፡ይለብሳሉ፤
የኃጢአተኞችም፡ድንኳን፡አይገኝም።

## ምዕራፍ፡፱።

፩፡ ኢዮብም፡መለሰ፡እንዲህም፡አለ፤—
፪፡ በእውነት፡እንዲህ፡እንደ፡ሆነ፡አወቅሁ፤
ሰውስ፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡ጻድቅ፡መሆን፡እንዴት፡ይችላል?
፫፡ ከእርሱ፡ጋር፡ይከራከር፡ዘንድ፡ቢወድድ÷
ከሺህ፡ነገር፡አንዱን፡መመለስ፡አይችልም።
፬፡ ልቡ፡ጠቢብ÷ኃይሉም፡ታላቅ፡ነው፤
ደፍሮትስ፡በደኅና፡የሄደ፡ማን፡ነው?
፭፡ ተራሮችን፡ይነቅላል፤አያውቁትም፤
በቍጣውም፡ይገለብጣቸዋል።
፮፡ ምድርን፡ከስፍራዋ፡ያናውጣታል÷
ምሰሶችዋም፡ይንቀጠቀጣሉ።
፯፡ ፀሐይን፡ያዝዛታል÷አትወጣምም፤
ከዋክብትንም፡ያትማል።
፰፡ ሰማያትን፡ብቻውን፡ይዘረጋል÷
በባሕሩም፡ማዕበል፡ላይ፡ይረግጣል።
፱፡ ድብ፡የሚባለውን፡ኮከብና፡አሪዮን፡የሚባለውን፡ኮከብ÷ሰባቱንም፡ከዋክብት÷
በደቡብም፡በኩል፡ያሉትን፡የከዋክብት፡ማደርያዎች፡ሠርቶአል።
፲፡ የማይመረመረውን፡ታላላቅ፡ነገር÷
የማይቈጠረውንም፡ተአምራት፡ያደርጋል።
፲፩፡ እነሆ÷ቢመጣብኝ፡አላየውም፤
ቢያልፍብኝም፡አላውቀውም።
፲፪፡ እነሆ÷ፈጥኖ፡ቢነጥቅ፡የሚከለክለው፡ማን፡ነው?
እርሱንስ፡— ምን፡ታደርጋለህ? የሚለው፡ማን፡ነው?

፲፫፡ እግዚአብሔር፡ቍጣውን፡አይመልስም፤
ከእርሱ፡በታች፡ረዓብን፡የሚረዱ፡ይዋረዳሉ።
፲፬፡ ይልቁንስ፡እመልስለት፡ዘንድ÷
ቃሌንስ፡በፊቱ፡እመርጥ፡ዘንድ፡እኔ፡ማን፡ነኝ?
፲፭፡ ጻድቅ፡ብሆን፡ኖሮ፡አልመልስለትም፡ነበር፤
ወደ፡ፈራጅም፡እለምን፡ነበር።

፲፮፡ ብጠራው ፡ እርሱም ፡ ቢመልስልኝ ፡ ኖሮ ፥
ቃሌን ፡ እንደ ፡ ሰማ ፡ አላምንም ፡ ነበር ።
፲፯፡ በዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ይሰብረኛል ፥
ቍስሌንም ፡ ያለ ፡ ምክንያት ፡ ያበዛል ።
፲፰፡ እተነፍስ ፡ ዘንድ ፡ አይተወኝም ፥
ነገር ፡ ግን ፡ መራራን ፡ ነገር ፡ እጥግበኛል ።
፲፱፡ የኃይል ፡ ነገር ፡ ቢሆን ፡ እርሱ ፡ ኃያል ፡ ነው ፤
የፍርድ ፡ ነገር ፡ ቢሆን ፡— ጊዜን ፡ ወሳኙ ፡ ማን ፡
ነው ? ይላል ።
፳፡ ጻድቅ ፡ ብሆን ፡ አፌ ፡ ይወቅሰኛል ፤
ፍጹምም ፡ ብሆን ፡ ጠማማ ፡ ያደርገኛል ።
፳፩፡ ፍጹም ፡ ነኝ ፡ ራሴንም ፡ አልመለከትም ፤
ሕይወቴንም ፡ እንቃታለሁ ።
፳፪፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ ነው ፤ ስለዚህ ፡—
ፍጹማንንና ፡ ክፉዎችን ፡ ያጠፋል ፡ እላለሁ ።
፳፫፡ መቅሠፍቱ ፡ ፈጥኖ ፡ ቢገድል ፥
በንጹሐን ፡ ፈተና ፡ ይሳለቃል ።
፳፬፡ ምድር ፡ በኃጥአን ፡ እጅ ፡ ተሰጥታለች ፤
የፈራጆችዋን ፡ ፊት ፡ ሸፍኖአል ፤
እርሱ ፡ ካልሆነ ፡ ማን ፡ ነው ?

፳፭፡ ዘመኔ ፡ ከሚሮጥ ፡ ሰው ፡ ይልቅ ፡ ይፈጥናል ፤
ይሸሻል ፥ መልካምንም ፡ አያይም ።
፳፮፡ የደንገል ፡ ታንኳ ፡ እንደሚፈጥን ፥
ንስርም ፡ ወደ ፡ ንጥቂያው ፡ እንደሚበርር ፡ ያል
ፋል ።
፳፯፡ እኔ ፡— የኀዘን ፡ እንጕርጕሮዬን ፡ እረሳለሁ ፤
ፊቴን ፡ መልሼ ፡ እጽናናለሁ ፡ ብል ፥
፳፰፡ ንጹሕ ፡ እንደማታደርገኝ ፡ እኔ ፡ አውቃለሁና ፡
ከመከራዬ ፡ ሁሉ ፡ እፈራለሁ ።
፳፱፡ በደለኛ ፡ እንደሚሆን ፡ ሰው ፡ እሆናለሁ ፤
ስለ ፡ ምንስ ፡ በከንቱ ፡ እደክማለሁ ?
፴፡ በአመዳይ ፡ ውስጥ ፡ ብታጠብ ፥
እጆቼንም ፡ እጅግ ፡ ባነጻ ፥
፴፩፡ በአዘቅት ፡ ውስጥ ፡ ታሰጥመኛለህ ፥
ልብሴም ፡ ይጸየፈኛል ።
፴፪፡ እንድመልስለት ፡ አብረን ፡ ወደ ፡ ፍርድ ፡ እን
ገባ ፡ ዘንድ ፥
እርሱ ፡ እንደ ፡ እኔ ፡ ሰው ፡ አይደለም ።
፴፫፡ እጁን ፡ በሁለታችን ፡ ላይ ፡ የሚያኖር ፡ ዳኛ ፡
በመካከላችን ፡ ምነው ፡ በተገኘ !
፴፬፡ በትሩን ፡ ከእኔ ፡ ላይ ፡ ያርቅ ፥
ግርማውም ፡ አያስፈራኝ ፤
፴፭፡ እናገርም ፡ ነበር ፥ አልፈራውምም ፡ ነበር ፤
በራሴ ፡ እንዲህ ፡ አይደለሁምና ።

ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፡ ነፍሴ ፡ ሕይወቴን ፡ ሰለቸችት ፤
የኀዘን ፡ እንጕርጕሮዬን ፡ እለቅቀዋለሁ ፤
በነፍሴም ፡ ምሬት ፡ እናገራለሁ ።
፪፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዲህ ፡ እለዋለሁ ፡—
አትፍረድብኝ ፤ የምትከራከረኝ ፡ ለምን ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ ንገረኝ ።
፫፡ ልታስጨንቅና ፡ የእጅህን ፡ ሥራ ፡ ልትንቅ ፡
የኃጥአንንስ ፡ ምክር ፡ ልታበራ ፡
በአንተ ፡ ዘንድ ፡ መልካም ፡ ነውን ?
፬፡ በውኑ ፡ የሥጋ ፡ ዓይን ፡ አለህን ?
ወይስ ፡ ሰው ፡ እንደሚያይ ፡ ታያለህን ?
፭፡፮፡ ወይስ ፡ ክፋቴን ፡ ትፈላለግ ፡ ዘንድ ፥
ኃጢአቴንም ፡ ትመረምር ፡ ዘንድ ፥
ዘመንህ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ዘመን ፡ ነውን ?
ወይስ ፡ ዓመታትህ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ዓመታት ፡
ናቸውን ?
፯፡ ከዚህም ፡ በላይ ፡ በደለኛ ፡ እንዳልሆንሁ ፥
ከእጅህም ፡ የሚያድን ፡ እንደሌለ ፡ አንተ ፡ ታው
ቃለህ ።
፰፡ እጅህ ፡ ለወሰችኝ ፡ ሠራችኝም ፤
ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ዞረህ ፡ ታጠፋኝ ፡ ዘንድ ፡
ፈለግህ ።
፱፡ እንደ ፡ ጭቃ ፡ አድርገህ ፡ እንደ ፡ ለወስኸኝ ፡
አስብ ፤
ወደ ፡ ትቢያም ፡ ትመልሰኛለህን ?
፲፡ በውኑ ፡ እንደ ፡ ወተት ፡ አላፈሰስኸኝምን ?
እንደ ፡ እርጎስ ፡ አላረጋኸኝምን ?
፲፩፡ ቁርበትና ፡ ሥጋ ፡ አለበስኸኝ ፥
በአጥንትና ፡ በጅማትም ፡ አጠነከርኸኝ ።
፲፪፡ ሕይወትና ፡ ቸርነት ፡ አደረግህልኝ ፤
መጐብኘትህም ፡ መንፈሴን ፡ ጠበቀች ።
፲፫፡ እነዚህንም ፡ ነገሮች ፡ በልብህ ፡ ውስጥ ፡ ሰወ
ርህ ፤
ይህ ፡ ሁሉ ፡ በአሳብህ ፡ እንዳለ ፡ አውቃለሁ ።
፲፬፡ ኃጢአት ፡ ብሠራ ፡ አንተ ፡ ትመለከተኛለህ ፤
ከኃጢአቴም ፡ ንጹሕ ፡ አታደርገኝም ።
፲፭፡ በደለኛ ፡ ብሆን ፡ ወዮልኝ ፤
ጻድቅም ፡ ብሆን ፡ ራሴን ፡ አላነሣም ፤
ጕስቍልናን ፡ ተሞልቻለሁ ፥
መከራዬንም ፡ ተመልክቻለሁ ።
፲፮፡ ራሴም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ቢል ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡
ታድነኛለህ ፤
ተመልሰህም ፡ ድንቅ ፡ ነገር ፡ታደርግብኛለህ ።
፲፯፡ ምስክሮችህን ፡ ታድስብኛለህ ፤
ቍጣህንም ፡ ታበዛብኛለህ ፤
ጭፍራ ፡ በጭፍራ ፡ ላይ ፡ ትጨምርብኛለህ ።

፲፰፡ ስለ ፡ ምን ፡ ከማኅፀን ፡ አወጣኸኝ ?
ዓይን ፡ ሳያየኝ ፡ ምነው ፡ በሞትሁ ።
፲፱፡ እንዳልነበረ ፡ በሆንሁ ፤
ከማኅፀንም ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ በወሰዱኝ ።
፳፡ የሕይወቴ ፡ ዘመን ፡ ጥቂት ፡ አይደለምን ?
፳፩፡ ወደማልመለስበት ፡ ስፍራ ፥
ወደ ፡ ጨለማና ፡ ወደ ፡ ሞት ፡ ጥላ ፡ ምድር ፥
፳፪፡ እንደ ፡ ጨለማም ፡ ወደ ፡ ጨለመች ፥
ሥርዓትም ፡ ወደሌለባት ፡ ወደ ፡ ሞት ፡ ጥላ ፥
ብርሃንዋም ፡ እንደ ፡ ጨለማ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡
ምድር ፡ ሳልሄድ ፥
ጥቂት ፡ እጽናና ፡ ዘንድ ፡ ተወኝ ፥ ልቀቀኝም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ፤ ነዕማታዊውም ፡ ሶፋር ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—
፪ ፤ በውኑ ፡ ለቃል ፡ ብዛት ፡ መልስ ፡ መስጠት ፡ አይገባምን ?
ወይስ ፡ ተናጋሪ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ጻድቅ ፡ ይቈጠራልን ?
፫ ፤ ትምክህትህስ ፡ ሰዎችን ፡ ዝም ፡ ያሰኛቸዋልን ?
ብትሳለቅስ ፡ የሚያሳፍርህ ፡ የለምን ?
፬ ፤ አንተ ፡— ትምህርቴ ፡ የተጣራ ፡ ነው ÷
በዓይንህም ፡ ፊት ፡ ንጹሕ ፡ ነኝ ፡ ትላለህ ።
፭ ፤ ምነው ፡ እግዚአብሔር ፡ ቢናገርህ !
በአንተም ፡ ላይ ፡ ከንፈሩን ፡ ቢከፍት !
፮ ፤ የጥበቡን ፡ ምሥጢር ፡ ቢገልጥልህ !
ማስተዋሉ ፡ ብዙ ፡ ነውና ።
እግዚአብሔር ፡ ለበደልህ ፡ ከሚገባው ፡ አሳንሶ ፡ እንደሚያስከፍልህ ፡ እወቅ ።

፯ ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ጥልቅ ፡ ነገር ፡ ልትመረምር ፡ ትችላለህን ?
ወይስ ፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ አምላክን ፡ ፈጽመህ ፡ ልትመረምር ፡ ትችላለህን ?
፰ ፤ ከሰማይ ፡ ይልቅ ፡ ከፍ ፡ ይላል ፤ ምን ፡ ልታደርግ ፡ ትችላለህ ?
ከሲኦልም ፡ ይልቅ ፡ ይጠልቃል ፤ ምን ፡ ልታውቅ ፡ ትችላለህ ?
፱ ፤ ርዝመቱ ፡ ከምድር ፡ ይልቅ ፡ ይረዝማል ÷
ከባሕርም ፡ ይልቅ ፡ ይሰፋል ።
፲ ፤ እርሱ ፡ ቢያልፍ ÷ ቢዘጋም ÷ ጉባኤንም ፡ ቢሰበስብ ÷
የሚከለክለው ፡ ማን ፡ ነው ?
፲፩ ፤ ምናምንቴዎችን ፡ ሰዎች ፡ ያውቃልና ÷
በደልንም ፡ ሲያይ ፡ ዝም ፡ ብሎ ፡ አይመለከትም ።
፲፪ ፤ የሜዳ ፡ አህያ ፡ ግልገል ፡ ሰው ፡ ሆኖ ፡ ቢወለድ ÷
ያን ፡ ጊዜ ፡ ከንቱ ፡ ሰው ፡ ጥበብን ፡ ያገኛል ።

፲፫ ፤ ፲፬ ፤ በእጅህ ፡ በደል ፡ ቢኖር ፡ አርቀው ፤
በድንኳንህም ፡ ኀጢአት ፡ አይኑር ፤
አንተ ፡ ልብህን ፡ ቅን ፡ ብታደርግ ÷
እጅህንም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ብትዘረጋ ÷
፲፭ ፤ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በእውነት ፡ ፊትህን ፡ ያለ ፡ ነውር ፡ ታነሣለህ ፤
ትበረታለህ ÷ አትፈራምም ።
፲፮ ፤ መከራህንም ፡ ትረሳለህ ፤
እንዳለፈ ፡ ውኃ ፡ ታስበዋለህ ።
፲፯ ፤ ከቀትር ፡ ይልቅ ፡ ሕይወትህ ፡ ይበራል ፤
ጨለማም ፡ ቢሆን ፡ እንደ ፡ ጥዋት ፡ ይሆናል ።
፲፰ ፤ ተስፋም ፡ ስላለህ ፡ ተዘልለህ ፡ ትቀመጣለህ ፤
በዙሪያህ ፡ ትመለከታለህ ÷ በደኅንነትም ፡ ታርፋለህ ።
፲፱ ፤ ትተኛለህ ÷ የሚያስፈራህም ፡ የለም ፤
ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ልመና ፡ ያቀርቡልሃል ።
፳ ፤ የክፉዎች ፡ ዓይን ፡ ግን ፡ ትጨልማለች ፤
የሚሸሹበትንም ፡ ያጣሉ ÷
ተስፋቸውም ፡ ነፍሳቸውን ፡ ማውጣት ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ ፤ ኢዮብም ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—
፪ ፤ በእርግጥ ፡ እናንተ ፡ ዓይነተኞች ፡ ሰዎች ፡ ናችሁ ፤
ጥበብም ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይሞታል ።
፫ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ እናንተ ፡ ማስተዋል ፡ አለኝ ፤
ከእናንተም ፡ የማንስ ፡ አይደለሁም ፤
እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ የማያውቅ ፡ ማን ፡ ነው ?
፬ ፤ እግዚአብሔርን ፡ የጠራሁ ፡ እርሱም ፡ የመለሰልኝ ፡ እኔ ፤
ለባልንጀራው ፡ መሳለቂያ ፡ እንደሚሆን ፡ ሰው ፡ ሆኛለሁ ፤
ጻድቅና ፡ ፍጹም ፡ ሰው ፡ መሳለቂያ ፡ ሆኖአል ።
፭ ፤ ተዘልሎ ፡ በሚቀመጥ ፡ ሰው ፡ አሳብ ፡ መከራ ፡ ይናቃል ፤
ነገር ፡ ግን ፡ እግሩን ፡ ሊያድጠው ፡ ተዘጋጅቶ ፡ አል ።
፮ ፤ የቀማኞች ፡ ድንኳን ፡ በደኅንነት ፡ ይኖራል ÷
እግዚአብሔርንም ፡ የሚያስቈጡ ፡ ተዘልለው ፡ ተቀምጠዋል ፤
እግዚአብሔር ፡ ሁሉን ፡ በእጃቸው ፡ አምጥቶላቸዋል ።

፯ ፤ አሁን ፡ ግን ፡ እንስሶችን ፡ ጠይቅ ÷ ያስተምሩህማል ፤
የሰማይንም ፡ ወፎች ፡ ጠይቅ ÷ ይነግሩህማል ።
፰ ፤ ወይም ፡ ለምድር ፡ ተናገር ÷ እርስዋም ፡ ታስተምርሃለች ፤
የባሕርም ፡ ዓሣዎች ፡ ይነግሩሃል ።
፱ ፤ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ይህን ፡ እንዳደረገ ፡
ከእነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የማያውቅ ፡ ማን ፡ ነው ?
፲ ፤ የሕያዋን ፡ ሁሉ ፡ ነፍስ ፡
የሰውም ፡ ሁሉ ፡ መንፈስ ፡ በእጁ ፡ ናት ።
፲፩ ፤ ምላስ ፡ መብልን ፡ እንደሚቀምስ ÷
ጆሮ ፡ ቃልን ፡ የሚለይ ፡ አይደለምን ?
፲፪ ፤ በሽምግልና ፡ ጊዜ ፡ ጥበብ ÷
በዘመንስ ፡ ርዝመት ፡ ማስተዋል ፡ ይገኛል ።

፲፫ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ጥበብና ፡ ኃይል ፡ አለ ፤
ለእርሱ ፡ ምክርና ፡ ማስተዋል ፡ አለው ።
፲፬ ፤ እነሆ ÷ ይፈርሳል ÷ የፈረሰውም ፡ ተመልሶ ፡ አይሠራም ፤
በሰውም ፡ ቢዘጋበት ፡ የሚከፍትለት ፡ የለም ።
፲፭ ፤ እነሆ ÷ ውኆቹን ፡ ይከለክላል ÷ እነርሱም ፡ ይደርቃሉ ፤
እንደ ፡ ገና ፡ ይሰድዳቸዋል ÷ ምድሪቱንም ፡ ይገለብጣሉ ።
፲፮ ፤ ኃይልና ፡ ጥበብ ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ናቸው ፤
የሚስተውና ፡ የሚያስተው ፡ ለእርሱ ፡ ናቸው ።
፲፯ ፤ መካሮችንም ፡ እንደ ፡ ዘረፋ ፡ ይወስዳቸዋል ÷

ፈራጆችንም ፡ ያሳብዳል ።
፲፰ ፡ የነገሥታትንም ፡ እስራት ፡ ይፈታል ÷
ወገባቸውንም ፡ በመታጠቂያ ፡ ያስራቸዋል ።
፲፱ ፡ ካህናትን ፡ እንደ ፡ ዘረፋ ፡ ይወስዳቸዋል ÷
ኃያላንንም ፡ ይገለብጣቸዋል ።
፳ ፡ ከታመኑ ፡ ሰዎችም ፡ ቋንቋን ፡ ያርቃል ÷
የሽማግሌዎችንም ፡ ማስተዋል ፡ ይወስድባቸዋል ።
፳፩ ፡ በአለቆች ፡ ላይ ፡ ንቀትን ፡ ያፈስሳል ÷
የብርቱዎችንም ፡ መታጠቂያ ፡ ያላላል ።
፳፪ ፡ ጥልቅ ፡ ነገር ፡ ከጨለማ ፡ ይገልጣል ÷
የሞትንም ፡ ጥላ ፡ ወደ ፡ ብርሃን ፡ ያወጣል ።
፳፫ ፡ አሕዛብን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ÷ እነርሱንም ፡ ያጠፋል ፤
አሕዛብንም ፡ ያሰፋል ÷ እነርሱንም ፡ ያፈልሳቸዋል ።
፳፬ ፡ ከምድር ፡ አሕዛብ ፡ አለቆች ፡ ዘንድ ፡ ማስተዋልን ፡ ይወስዳል ÷
መንገድም ፡ በሌለበት ፡ በረሃ ፡ ያቅበዘብዛቸዋል ።
፳፭ ፡ ብርሃንም ፡ ሳይኖር ፡ በጨለማ ፡ ይርመሰመሳሉ ፤
እንደ ፡ ሰካራም ፡ ይቅበዘበዛሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ ፡ እነሆ ÷ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ዓይኔ ፡ አየች ፤
ጆሮዬም ፡ ሰምታ ፡ አስተዋለችው ።
፪ ፡ እናንተ ፡ የምታውቁትን ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ አውቃለሁ ፤
ከእናንተ ፡ የማንስ ፡ አይደለሁም ።
፫ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡ ለሚችል ፡ አምላክ ፡ መናገር ፡ እፈልጋለሁ ÷
ከእግዚአብሔርም ፡ ጋር ፡ ለመዋቀስ ፡ እሻለሁ ።
፬ ፡ እናንተ ፡ ግን ፡ በሐሰት ፡ ለባጮች ፡ ናችሁ ፤
ሁላችሁ ፡ የማትጠቅሙ ፡ ባለ ፡ መድኃኒቶች ፡ ናችሁ ።
፭ ፡ ምነው ፡ ዝም ፡ ብላችሁ ፡ ብትኖሩ !
ይህ ፡ ጥበብ ፡ በሆነላችሁ ፡ ነበር ።
፮ ፡ አሁንም ፡ ክርክሬን ፡ ስሙ ÷
የከንፈሬንም ፡ ሙግት ፡ አድምጡ ።
፯ ፡ በውኑ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሐሰትን ፡ ትናገራላችሁን ?
ስለ ፡ እርሱም ፡ ሽንገላን ፡ ታወራላችሁን ?
፰ ፡ ለፊቱስ ፡ ታደላላችሁን ?
ስለ ፡ እግዚአብሔርስ ፡ ትከራከራላችሁን ?
፱ ፡ ቢመረምራችሁስ ፡ መልካም ፡ ይሆንላችኋልን ?
ወይስ ፡ በሰው ፡ እንደምትሳለቁ ፡ ትሳለቁበታላችሁን ?
፲ ፡ በስውር ፡ ለሰው ፡ ፊት ፡ ብታደሉ ፡
ዘለፋ ፡ ይዘልፋችኋል ።
፲፩ ፡ ክብሩስ ፡ አያስፈራችሁምን ?
ግርማውስ ፡ አይወድቅባችሁምን ?
፲፪ ፡ ምሳሌዎቻችሁ ፡ የአመድ ፡ ምሳሌዎች ፡ ናቸው ፤
ምሽጎቻችሁ ፡ የጭቃ ፡ ምሽጎች ፡ ናቸው ።

፲፫ ፡ ዝም ፡ በሉ ÷ እናገርም ፡ ዘንድ ፡ ተዉኝ ፤
የሆነው ፡ ነገር ፡ ይምጣብኝ ።
፲፬ ፡ ሥጋዬን ፡ በጥርሴ ፡ እይዛለሁ ÷
ሕይወቴንም ፡ በእጄ ፡ አኖራለሁ ።
፲፭ ፡ እነሆ ÷ ቢገድለኝ ፡ ስንኳ ፡ እርሱን ፡ በትዕግሥት ፡ እጠባበቃለሁ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ መንገዴን ፡ በፊቱ ፡ አጸናለሁ ።
፲፮ ፡ ዝንጉ ፡ ሰው ፡ በፊቱ ፡ አይገባምና ፡
እርሱ ፡ መድኃኒት ፡ ይሆንልኛል ።
፲፯ ፡ ነገሬን ፡ ተግታችሁ ፡ ስሙ ÷
ምስክርነቴንም ፡ በጆሮአችሁ ፡ አድምጡ ።
፲፰ ፡ እነሆ ÷ ሙግቴን ፡ አዘጋጅቻለሁ ።
እንደምጸድቅም ፡ አውቃለሁ ።
፲፱ ፡ ከእኔስ ፡ ጋር ፡ የሚፋረድ ፡ ማን ፡ ነው ?
አሁን ፡ እኔ ፡ ዝም ፡ ብል ፡ እሞታለሁ ።

፳ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ሁለት ፡ ነገር ፡ አታድርግብኝ ፤
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከፊትህ ፡ አልሰወርም ፤
፳፩ ፡ እጅህን ፡ ከእኔ ፡ አርቅ ፤
ግርማህም ፡ አታስደንግጠኝ ።
፳፪ ፡ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ጥራኝ ÷ እኔም ፡ እመልስልሃለሁ ።
ወይም ፡ እኔ ፡ ልናገር ÷ አንተም ፡ መልስልኝ ።
፳፫ ፡ ያለብኝስ ፡ በደልና ፡ ኃጢአት ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ነው ?
መተላለፌንና ፡ ኃጢአቴን ፡ አስታውቀኝ ።
፳፬ ፡ ፊትህን ፡ ከእኔ ፡ የሰወርህ ÷
እንደ ፡ ጠላትህም ፡ የቈጠርኸኝ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ነው ?
፳፭ ፡ የረገፈውን ፡ ቅጠል ፡ ታስጨንቃለህን ?
ወይስ ፡ የደረቀውን ፡ ዕብቅ ፡ ታሳድዳለህን ?
፳፮ ፡ የመረረ ፡ ነገር ፡ ጽፈህብኛልና ፤
የሕፃንነቴንም ፡ ኃጢአት ፡ ታወርሰኛለህ ።
፳፯ ፡ እግሬንም ፡ በእግር ፡ ግንድ ፡ አግብተሃል ÷
መንገዴንም ፡ ሁሉ ፡ መርምረሃል ፤
የእግሬን ፡ ፍለጋ ፡ ወስነሃል ።
፳፰ ፡ እኔ ፡ እንደሚጠፋ ፡ በስባሳ ፡ ነገር ÷
ብልም ፡ እንደሚበላው ፡ ልብስ ፡ ነኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ ፡ ከሴት ፡ የተወለደ ፡ ሰው ፡
የሕይወቱ ፡ ዘመን ፡ ጥቂት ፡ ቀን ፡ ነው ÷ መከራም ፡ ይሞላዋል ።
፪ ፡ እንደ ፡ አበባ ፡ ይወጣል ÷ ይረግፋልም ፤
እንደ ፡ ጥላም ፡ ይሸሻል ÷ እርሱም ፡ አይጸናም ።
፫ ፡ እንደዚህስ ፡ ባለ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ዓይኖችህን ፡ ትከፍታለህን ?
ከአንተስ ፡ ጋር ፡ እኔን ፡ ወደ ፡ ፍርድ ፡ ታገባለህን ?
፬ ፡ ከርኩስ ፡ ነገር ፡ ንጹሕን ፡ ሊያወጣ ፡ ማን ፡ ይችላል ?
አንድ ፡ እንኳ ፡ የሚችል ፡ የለም ።
፭ ፡ የሰው ፡ ዕድሜ ፡ የተወሰነ ፡ ነው ÷
የወሩም ፡ ቍጥር ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ነው ÷
እርሱም ፡ ሊተላለፈው ፡ የማይችለውን ፡ ዳርቻ ፡ አደረግህለት ።
፮ ፡ እንደ ፡ ምንደኛ ፡ ዕድሜው ፡ እስኪፈጸም ፡

ድረስ ÷
ያርፍ ፡ ዘንድ ፡ ከእርሱ ፡ ጥቂት ፡ ዘወር ፡ በል ።

፯ ዛፍ ፡ ቢቈረጥ ፡ ደግሞ ፡ ያቈጠቍጥ ፡ ዘንድ ÷
ቅርንጫፉም ፡ እንዳያልቅ ፡ ተስፋ ፡ አለው ።
፰ ሥሩም ፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡ ቢያረጅ ÷
ግንዱም ፡ በመሬት ፡ ውስጥ ፡ ቢሞት ÷
፱ ከውኃ ፡ ሽታ ፡ የተነሣ ፡ ያቈጠቍጣል ፤
እንደ ፡ አትክልት ፡ ቅርንጫፍ ፡ ያወጣል ።
፲ ሰው ፡ ግን ፡ ይሞትና ፡ ይጋደማል ፤
ሰውም ፡ ነፍሱን ፡ ይሰጣል ÷ እርሱስ ፡ ወዴት ፡ አለ ?
፲፩ ውኃ ፡ ከባሕር ፡ ውስጥ ፡ ያልቃል ፤
ወንዙም ፡ ያንሳል ፡ ይደርቅማል ።
፲፪ ሰውም ፡ ተኝቶ ፡ አይነሣም ፤
ሰማይ ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፡ አይነቃም ÷
ከእንቅልፉም ፡ አይነሣም ።

፲፫ በሲኦል ፡ ውስጥ ፡ ምነው ፡ በሰወርኸኝ ፡ ኖሮ !
ቍጣህ ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፡ በሸሸግኸኝ ፡ ኖሮ !
ቀጠሮም ፡ አድርገህ ፡ ምነው ፡ ባሰብኸኝ ፡ ኖሮ !
፲፬ በውኑ ፡ ሰው ፡ ከሞተ ፡ ተመልሶ ፡ ሕያው ፡ ይሆናልን ?
መለወጤ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ÷
የሰልፌን ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ በትዕግሥት ፡ በተጠባበቅሁ ፡ ነበር ።
፲፭ በጠራኸኝና ፡ በመለስሁልህ ፡ ነበር ፤
የእጅህንም ፡ ሥራ ፡ በተመኘኸው ፡ ነበር ።
፲፮ አሁን ፡ ግን ፡ እርምጃዬን ፡ ቈጥረኸዋል ፤
ኃጢአቴንም ፡ ትጠባበቃለህ ።
፲፯ መተላለፌ ፡ በከረጢት ፡ ውስጥ ፡ ታትሞአል ÷
ኃጢአቴንም ፡ ለብጠህበታል ።

፲፰ ተራራ ፡ ሲወድቅ ፡ ይጠፋል ÷
ዓለቱም ፡ ከስፍራው ፡ ይፈልሳል ፤
፲፱ ውኆች ፡ ድንጋዮቹን ፡ ይፍቃሉ ፤
ፈሳሾቹም ፡ የምድሩን ፡ አፈር ፡ ይወስዳሉ ፤
እንዲሁ ፡ የሰውን ፡ ተስፋ ፡ ታጠፋዋለህ ።
፳ ለዘላለም ፡ ታሸንፈዋለህ ÷ እርሱም ፡ ያልፋል ፤
ፊቱን ፡ ትለውጣለህ ÷ እርሱንም ፡ ትሰድደዋለህ ።
፳፩ ልጆቹ ፡ ቢከብሩ ፡ አያውቅም ፤
ቢዋረዱም ፡ አያይም ።
፳፪ ነገር ፡ ግን ፡ የገዛ ፡ ሥጋው ፡ ሕመም ፡ ብቻ ፡ ይሰማዋል ÷
ለራሱም ፡ ብቻ ፡ ያለቅሳል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ ቴማናዊውም ፡ ኤልፋዝ ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦
፪ በውኑ ፡ ጠቢብ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ነፋስ ፡ በሆነ ፡ እውቀት ፡ ይመልሳልን ?
በሆዱስ ፡ የምሥራቅን ፡ ነፋስ ፡ ይሞላልን ?
፫ ከማይረባ ፡ ነገር ÷
ወይስ ፡ ከማይጠቅም ፡ ንግግር ፡ ጋር ፡ ይዋቀሳልን ?
፬ አንተም ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ታፈርሳለህ ፤
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አምልኮን ፡ ታስቀራለህ ።
፭ በደልህ ፡ አፍህን ፡ ያስተምረዋል ÷
የተንኰለኞችንም ፡ አንደበት ፡ ትመርጣለህ ።
፮ የሚፈርድብህ ፡ አፍህ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እኔ ፡ አይደለሁም ፤
ከንፈሮችህም ፡ ይመሰክሩብሃል ።

፯ በውኑ ፡ መጀመሪያ ፡ የተወለድህ ፡ ሰው ፡ አንተ ፡ ነህን ?
ወይስ ፡ ከተራሮች ፡ በፊት ፡ ተፀንሰህን ?
፰ የእግዚአብሔርንስ ፡ ምሥጢር ፡ ሰምተሃልን ?
ወይስ ፡ ጥበብን ፡ ለብቻህ ፡ አድርገሃልን ?
፱ እኛ ፡ የማናውቀውን ፡ አንተ ፡ የምታውቀው ፡ ምንድር ፡ ነው ?
ከእኛ ፡ ዘንድስ ፡ የሌለው ፡ የምታስተውለው ፡ ምንድር ፡ ነው ?
፲ በዕድሜ ፡ ከአባትህ ፡ የሚበልጡ ፡
ሽበትም ፡ ያላቸው ፡ ሽማግሌዎችም ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ አሉ ።
፲፩ በውኑ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማጽናናት ÷
በየዋሃትም ፡ የተነገረህ ፡ ቃል ፡ ጥቂት ፡ ነውን ?
፲፪ ልብህስ ፡ ለምን ፡ ይወስድሃል ?
ዓይኖችህስ ፡ ለምን ፡ ይገለምጣሉ ?
፲፫ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ መንፈስህን ፡ እስከ ፡ ማንሣት ፡ ደርሰህ ፤
ይህንም ፡ ቃል ፡ ከአፍህ ፡ እስከ ፡ ማውጣት ፡ ደርሰህ ።
፲፬ ንጹሕ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ሰው ፡ ምንድር ፡ ነው ?
ጻድቅስ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ከሴት ፡ የተወለደ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
፲፭ እነሆ ÷ በቅዱሳኑ ፡ ስንኳ ፡ አይታመንም ፤
ሰማያትም ፡ በፊቱ ፡ ንጹሐን ፡ አይደሉም ።
፲፮ ይልቁንስ ፡ አስጸያፊና ፡ የረከሰ ÷
ኃጢአትንም ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ የሚጠጣ ፡ ሰው ፡ ምንኛ ፡ ያንስ ?

፲፯፲፰ ምድሪቱ ፡ ለብቻቸው ፡ ተሰጥታ ፡ የነበረች ÷
፲፱ በመካከላቸውም ፡ እንግዳ ፡ ያልገባባቸው ፡ ጠቢባን ፡
ከአባቶቻቸው ፡ ተቀብለው ፡ የተናገሩትን ፡ ያልሸሸጉትንም ÷
እገልጥልሃለሁ ÷ ስማኝ ፤ ያየሁትንም ፡ እነግርሃለሁ ።
፳ ክፉ ፡ ሰው ፡ ዕድሜውን ፡ ሙሉ ÷
ለግፈኛ ፡ በተመደቡለት ፡ በዓመታት ፡ ሁሉ ፡ በሕመም ፡ ይጣጣራል ።
፳፩ የሚያስደነግጥ ፡ ድምፅ ፡ በጆሮው ፡ ነው ፤
በደኅንነቱም ፡ ሳለ ፡ ቀማኛ ፡ ይመጣበታል ።
፳፪ ከጨለማ ፡ ተመልሶ ፡ እንዲወጣ ፡ አያምንም ÷
ሰይፍም ፡ ይሸምቅበታል ።
፳፫ ተቅበዝባዥም ፦ ወዴት ፡ አለ ? እያለ ፡ እንጀራ ፡

ይለምናል ፤
የጨለማ ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ቀረበበት ፡ ያውቃል ።
፳፬ መከራና ፡ ጭንቀት ፡ ያስፈራሩታል ፤
ለሰልፍ ፡ እንደ ፡ ተዘጋጀ ፡ ንጉሥ ፡ ያሸንፉታል ።
፳፭ እጁን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ዘርግቶአልና ፥
ሁሉንም ፡ በሚችል ፡ አምላክ ፡ ላይ ፡ ደፍሮአልና ፥
፳፮ በደንዳና ፡ አንገቱና ፡ በወፍራሙ ፡ በጋሻው ፡
ጕብጕብ ፡ እየሠገገ ፡ ይመጣበታልና ፥
፳፯ በስብም ፡ ፊቱን ፡ ከድኖአልና ፥
ስቡንም ፡ በወገቡ ፡ ላይ ፡ አድርጓልና ፥
፳፰ በተፈቱም ፡ ከተሞች ፡ ውስጥ ፥
ሰውም ፡ በሌለባቸው ፥
ክምር ፡ ለመሆን ፡ በተመደቡ ፡ ቤቶች ፡ ውስጥ ፡
ተቀምጦአልና ፡
፳፱ በለጠጋ ፡ አይሆንም ፥ ሀብቱም ፡ አይጸናም ፤
ጥላውንም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አይጥልም ፤
፴ ከጨለማ ፡ አይወጣም ፤
ነበልባሉም ፡ ቅርንጫፎቹን ፡ ያደርቃቸዋል ፥
አበባዎቹም ፡ ይረግፋሉ ።
፴፩ ዋጋው ፡ ከንቱ ፡ ነገር ፡ ይሆናልና ፡
ራሱን ፡ እያሳተ ፡ በከንቱ ፡ ነገር ፡ አይታመን ።
፴፪ ቀኑ ፡ ሳይደርስ ፡ ጊዜው ፡ ይፈጸማል ፥
ቅርንጫፉም ፡ አይለመልምም ።
፴፫ እንደ ፡ ወይን ፡ ያልበሰለውን ፡ ዘለላ ፡ ያረግፋል ፤
እንደ ፡ ወይራ ፡ አበባውን ፡ ይጥላል ።
፴፬ የዝንጉዎች ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ ለጥፋት ፡ ይሆናል ፥
የጉቦ ፡ ተቀባዮችንም ፡ ድንኳን ፡ እሳት ፡ ትበላ
ለች ።
፴፭ ጉዳትን ፡ ይፀንሳሉ ፥ በደልንም ፡ ይወልዳሉ ፥
ሆዳቸውም ፡ ተንኰልን ፡ ያዘጋጃል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ ኢዮብም ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦
፪ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ዓይነት ፡ ነገር ፡ እጅግ ፡ ሰማሁ ፤
እናንተ ፡ ሁላችሁ ፡ የምታደክሙ ፡ አጽናኞች ፡
ናችሁ ።
፫ በውኑ ፡ ከንቱ ፡ ቃል ፡ ይፈጸማልን ?
ወይስ ፡ ትመልስ ፡ ዘንድ ፡ ያነሣሣህ ፡ ምንድር ፡
ነው ?
፬ እኔ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ እናንተ ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡
ይቻለኝ ፡ ነበር ፤
ነፍሳችሁ ፡ በነፍሴ ፡ ፋንታ ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፥
እኔ ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ቃል ፡ ማሳከት ፥
ራሴንም ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ መነቅነቅ ፡ በተቻ
ለኝ ፡ ነበር ።
፭ በአፌም ፡ ነገር ፡ ባበረታኋችሁ ፡ ነበር ፤
የከንፈሬን ፡ ማጽናናት ፡ በልከለከልሁም ፡ ነበር ።
፮ እኔ ፡ ብናገር ፡ ሕማሜ ፡ አይቀነስም ፤
ዝምም ፡ ብል ፡ ከእኔ ፡ አይወገድም ።
፯ አሁን ፡ ግን ፡ አድክሞኛል ፤
ወገኔንም ፡ ሁሉ ፡ አፍርሰሃል ።
፰ መጨማተሬ ፡ ይመሰክርብኛል ፤
ክሳቴም ፡ ተነሥቶብኛል ፤
በፊቴም ፡ ይመሰክርብኛል ።
፱ በቍጣው ፡ ቀደደኝ ፥ እርሱም ፡ ጠላኝ ፤
ጥርሶቹንም ፡ አፋጨብኝ ፤
ጠላቴ ፡ ዓይኑን ፡ አፈጠጠብኝ ።
፲ እነርሱም ፡ አፋቸውን ፡ ከፈቱብኝ ፤
እያላገጡ ፡ ጕንጬን ፡ ጠፈጠፉኝ ፤
በአንድነትም ፡ ተሰበሰቡብኝ ።
፲፩ እግዚአብሔር ፡ ለጠማማ ፡ ሰው ፡ አሳልፎ ፡
ሰጠኝ ፥
በክፉዎችም ፡ እጅ ፡ ጣለኝ ።
፲፪ ተዘልዬ ፡ ተቀምጬ ፡ ነበር ፥ እርሱም ፡ ሰበረኝ ፤
አንገቴንም ፡ ይዞ ፡ ቀጠቀጠኝ ፤
እንደ ፡ ዓላማ ፡ አድርጎ ፡ አቆመኝ ።
፲፫ ቀስተኞቹ ፡ ከበቡኝ ፤
ኵላሊቴንም ፡ ቈራረጠ ፥ እርሱም ፡ አልራራም ፤
ሐሞቴን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አፈሰሰ ።
፲፬ በቍስል ፡ ላይ ፡ ቍስል ፡ ጨመረብኝ ፤
እንደ ፡ ኃያል ፡ እየሠገገ ፡ ይሮጥብኛል ።
፲፭ በቁርበቴ ፡ ላይ ፡ ማቅ ፡ ሰፋሁ ፥
ቀንዴንም ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ አኖርሁ ።
፲፮ ፊቴ ፡ ከልቅሶ ፡ የተነሣ ፡ ቀላ ፤
የሞት ፡ ጥላ ፡ በዓይኖቼ ፡ ቆብ ፡ ላይ ፡ አለ ፤
፲፯ ነገር ፡ ግን ፡ በእጄ ፡ ዓመፅ ፡ የለም ፤
ጸሎቴም ፡ ንጹሕ ፡ ነው ።
፲፰ ምድር ፡ ሆይ ፥ ደሜን ፡ አትክደኚ ፥
ለጩኸቴም ፡ ማረፊያ ፡ አይሁን ።
፲፱ አሁንም ፥ እነሆ ፥ ምስክሬ ፡ በሰማይ ፡ አለ ፥
የሚመሰክርልኝም ፡ በአርያም ፡ ነው ።
፳ ጸሎቴ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይድረስ ፥
ዓይኔም ፡ በፊቱ ፡ እንባ ፡ ታፍስስ ።
፳፩ የሰው ፡ ልጅ ፡ ከባልንጀራው ፡ ጋር ፡ እንደሚም
ዋገት ፥
ሰው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለመምዋገት ፡
ምነው ፡ በቻለ !
፳፪ ጥቂቶች ፡ ዓመታት ፡ ካለፉ ፡ በኋላ ፡
እኔ ፡ ወደማልመለስበት ፡ መንገድ ፡ እሄዳለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ መንፈሴ ፡ ደከመ ፥ ዘመኔ ፡ አለቀ ፥
መቃብርም ፡ ተዘጋጅቶልኛል ።
፪ አላጋጮች ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ አሉ ፥
ዓይኔም ፡ በማስቈጣታቸው ፡ አደረች ።
፫ አሁንም ፡ አንተ ፡ መያዣ ፡ ሆነህ ፡ ተዋሰኝ ፤
ከእኔ ፡ ጋር ፡ አጋና ፡ የሚመታ ፡ ማን ፡ ነው ?
፬ ልባቸውም ፡ እንዳያስተውል ፡ ከልክለኸዋል ፤
ስለዚህ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አታደርጋቸውም ።
፭ ለብዝበዛ ፡ ባልንጀሮቹን ፡ አሳልፎ ፡ የሚሰጥ ፡
ሰው ፥
የልጆቹ ፡ ዓይን ፡ ይጨልማል ።
፮ ለሕዝብም ፡ ምሳሌ ፡ አደረገኝ ፤
በፊቱ ፡ ላይ ፡ ጺቅ ፡ እንደሚሉበት ፡ ሰው ፡ ሆንሁ ።
፯ ዓይኔም ፡ ከኀዘን ፡ የተነሣ ፡ ፈዘዘች ፥
ብልቶቼም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ሆኑ ።

፰፤ ቅኖች ፡ ሰዎች ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ይደነቃሉ ፥
ንጹሕም ፡ በዝንጉው ፡ ላይ ፡ ይበሳጫል ።
፱፤ ጻድቅ ፡ ግን ፡ መንገዱን ፡ ያጠነክራል ፥
እጁም ፡ ንጹሕ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ኃይልን ፡ እየጨመረ ፡ ይሄዳል ።
፲፤ ነገር ፡ ግን ፡ እናንተ ፡ ሁሉ ፡ ተመልሳችሁ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ኑ ፤
በእናንተም ፡ ዘንድ ፡ ብልሃተኛ ፡ አላገኝም ።
፲፩፤ ዕድሜዬ ፡ አለፈች ፤
አሳቤና ፡ የልቤ ፡ መሣርያ ፡ ተቈረጠ ።
፲፪፤ ሌሊቱን ፡ ወደ ፡ ቀን ፡ ይለውጣሉ ፤
ብርሃኑም ፡ ወደ ፡ ጨለማ ፡ የቀረበ ፡ ይመስላቸዋል ።
፲፫፤ ተስፋ ፡ ባደርግ ፡ ሲኦል ፡ ቤቴ ፡ ናት ፤
ምንጣፌንም ፡ በጨለማ ፡ ዘርግቻለሁ ።
፲፬፤ መበስበስን ፦ አንተ ፡ አባቴ ፡ ነህ ፤
ትልንም ፦ አንቺ ፡ እናቴ ፡ እኅቴም ፡ ነሽ ፡ ብያለሁ ።
፲፭፤ እንግዲህ ፡ ተስፋዬ ፡ ወዴት ፡ ነው ?
ተስፋዬንስ ፡ የሚያይ ፡ ማን ፡ ነው ?
፲፮፤ አብረን ፡ በመሬት ፡ ውስጥ ፡ ስናርፍ ፥
ወደ ፡ ሲኦል ፡ ይወርዳል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩፤ ሹሐዊውም ፡ በልዳዶስ ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦
፪፤ እስከ ፡ መቼ ፡ ቃልን ፡ ታጠምዳለህ ?
አስተውል ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እንናገራለን ።
፫፤ ስለ ፡ ምንስ ፡ እንደ ፡ እንስሶች ፡ ተቈጠርን ?
ስለ ፡ ምንስ ፡ በዓይንህ ፡ ፊት ፡ ረከስን ?
፬፤ ቍጣ ፡ ወርሶሃል ፤ አንተስ ፡ የሞትህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥
ምድር ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ በድጣ ፡ ትሆናለችን ?
ወይስ ፡ ዓለት ፡ ከስፍራው ፡ ይነቀላልን ?

፭፤ የኃጢአተኛ ፡ መብራት ፡ ይጠፋል ፥
የእሳቱም ፡ ነበልባል ፡ ብልጭ ፡ አይልም ።
፮፤ ብርሃን ፡ በድንኳኑ ፡ ውስጥ ፡ ይጨልማል ፥
መብራቱም ፡ በላዩ ፡ ይጠፋል ።
፯፤ የኃይሉም ፡ እርምጃ ፡ ትጠብባለች ፥
ምክሩም ፡ ትጥለዋለች ።
፰፤ እግሩ ፡ በወጥመድ ፡ ትያዛለች ፥
በመረብም ፡ ላይ ፡ ይሄዳል ።
፱፤ አሽክላ ፡ ሰኰናውን ፡ ይይዛል ፥
ወስፈንጠርም ፡ ይበረታበታል ።
፲፤ በምድር ፡ ላይ ፡ የሸምቀቆ ፡ ገመድ ፥
በመንገዱም ፡ ላይ ፡ ወጥመድ ፡ ለእርሱ ፡ ተሰውራለች ።
፲፩፤ ድንጋጤ ፡ በዙሪያው ፡ ታስፈራዋለች ፥
በስተ ፡ ኋላውም ፡ ሆና ፡ ታባርረቸዋለች ።
፲፪፤ ኃይሉ ፡ በራብ ፡ ትደክማለች ፥
መቅሠፍትም ፡ እስኪሰናከል ፡ ተዘጋጅቶለታል ።
፲፫፤ የሰውነቱ ፡ ብልቶች ፡ ይጠፋሉ ፤
የሞትም ፡ በኵር ፡ ልጅ ፡ ብልቶቹን ፡ ይበላል ።
፲፬፤ ከሚታመንበት ፡ ድንኳን ፡ ይነቀላል ፤
ወደ ፡ ድንጋጤም ፡ ንጉሥ ፡ ያስቸኩሉታል ።
፲፭፤ በድንኳኑ ፡ ውስጥ ፡ ለእርሱ ፡ የማይሆነው ፡ ይኖራል ፤
በመኖሪያውም ፡ ላይ ፡ ዲን ፡ ይበተናል ።
፲፮፤ ሥሩ ፡ ከበታቹ ፡ ይደርቃል ፥
ጫፉም ፡ ከበላይ ፡ ይረግፋል ።
፲፯፤ መታሰቢያው ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ ይጠፋል ፥
በሜዳም ፡ ስም ፡ አይቀርለትም ።
፲፰፤ ከብርሃን ፡ ወደ ፡ ጨለማ ፡ ያፈልሱታል ፥
ከዓለምም ፡ ያሳድዱታል ።
፲፱፤ ዘርም ፡ ትውልድም ፡ በሕዝቡ ፡ መካከል ፡ አይሆንለትም ፤
በመኖሪያውም ፡ ውስጥ ፡ የሚቀመጥ ፡ ሰው ፡ አይቀርለትም ።
፳፤ የፊተኞች ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ደነገጡ ፥
እንዲሁ ፡ የኋለኞች ፡ ሰዎች ፡ ስለ ፡ ዘመኑ ፡ ይደነቃሉ ።
፳፩፤ በእውነት ፡ የኃጢአተኞች ፡ ቤት ፡ እንዲሁ ፡ ናት ፥
እግዚአብሔርንም ፡ የማያውቅ ፡ ሰው ፡ ስፍራ ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩፤ ኢዮብም ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦
፪፤ ነፍሴን ፡ የምትነዘንዙ ፥
በቃልስ ፡ የምታደቅቁኝ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ?
፫፤ ይኸው ፡ ስትሰድቡኝ ፡ አሥር ፡ ጊዜ ፡ ነው ፤
ስታሳክሩኝም ፡ አላፈራችሁም ።
፬፤ በእውነትም ፡ የሳትሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥
ስሕተቴ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ትኖራለች ።
፭፤ በእውነትም ፡ ብትኰሩብኝ ፥
መዋረዴን ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ብትከራከሩ ፥
፮፤ እንግዲህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ገለበጠኝ ፥
በመረቡም ፡ እንደ ፡ ከበበኝ ፡ እወቁ ።

፯፤ እነሆ ፥ ስለ ፡ ተደረገብኝ ፡ ግፍ ፡ ብጮኽ ፡ ማንም ፡ አይመልስልኝም ፤
እሰምቼም ፡ ብጠራ ፡ ፍርድ ፡ የለኝም ።
፰፤ እንዳላልፍ ፡ መንገዴን ፡ ዘግቶታል ፥
በጎዳናዬም ፡ ጨለማ ፡ አኑሮበታል ።
፱፤ ክብሬን ፡ ገፈፈኝ ፥
ዘውዴንም ፡ ከራሴ ፡ ላይ ፡ ወሰደ ።
፲፤ በዚህና ፡ በዚያም ፡ አፈረሰኝ ፥ እኔም ፡ ሄድሁ ፤
ተስፋዬንም ፡ እንደ ፡ ዛፍ ፡ ነቀለው ።
፲፩፤ ቍጣውንም ፡ አነደደብኝ ፥
እንደ ፡ ጠላቱም ፡ ቈጠረኝ ።
፲፪፤ ሠራዊቱ ፡ አብረው ፡ መጡ ፥
መንገዳቸውንም ፡ በላዬ ፡ አዘጋጁ ፥
በድንኳኔም ፡ ዙሪያ ፡ ሰፈሩ ።

፲፫፤ ወንድሞቼን ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ አራቀ ፥
የሚያውቁኝም ፡ አጥብቀው ፡ ተለዩኝ ።
፲፬፤ ዘመዶቼ ፡ ተቋረጡ ፥
ወዳጆቼም ፡ ረሱኝ ።

፲፭፤ ቤተ ፡ ሰቦቼና ፡ ሴቶች ፡ ባሪያዎቼ ፡ እንደ ፡ መጻ
ተኛ ፡ ቈጠሩኝ ፤
በዓይናቸውም ፡ እንደ ፡ እንግዳ ፡ ሆንሁ ።
፲፮፤ ባሪያዬን ፡ ብጠራ ÷ በአፌም ፡ ብቈላምጥ ፡ አይ
መልስልኝም ።
፲፯፤ ሚስቴ ፡ እስትንፋሴን ፡ ጠላች ÷
የእናቴም ፡ ማኅፀን ፡ ልጆች ፡ ልመናዬን ፡ ጠሉ ።
፲፰፤ ሕፃናቶች ፡ እንኳ ፡ አጠቁኝ ፤
ብነሣም ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ይናገራሉ ።
፲፱፤ አማካሪዎቼ ፡ ሁሉ ፡ ተጸየፉኝ ፤
እኔ ፡ የምወድዳቸው ፡ በላዬ ፡ ተገለበጡ ።
፳፤ አጥንቴ ፡ ከቍርበቴና ፡ ከሥጋዬ ፡ ጋራ ፡ ተጣበቀ ፤
ድድ ፡ ብቻ ፡ ቀርቶልኝ ፡ አመለጥሁ ።
፳፩፤ እናንተ ፡ ወዳጆቼ ፡ ሆይ ÷ ማሩኝ ፤
የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ መትታኛለችና ፡ ማሩኝ ።
፳፪፤ ስለ ፡ ምን ፡ እናንተ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ታሳድዱኛላችሁ ?
ከሥጋዬስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አትጠግቡም ?

፳፫፤ ምነው ፡ አሁን ፡ ቃሌ ፡ ቢጻፍ !
ምነው ፡ በመጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ ቢታተም !
፳፬፤ ምነው ፡ በብረት ፡ ብርና ፡ በእርሳስ ፡
በዓለቱ ፡ ላይ ፡ ለዘላለም ፡ ቢቀረጽ !
፳፭፤ እኔን ፡ ግን ፡ የሚቤዠኝ ፡ ሕያው ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷
በመጨረሻም ፡ ዘመን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እን
ዲቆም ÷
፳፮፤ ይህ ፡ ቍርበቴም ፡ ከጠፋ ፡ በኋላ ÷
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከሥጋዬ ፡ ተለይቼ ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ እንዳይ ፡ አውቃለሁ ፤
፳፯፤ እኔ ፡ ራሴ ፡ አየዋለሁ ÷
ዓይኖቼም ፡ ይመለከቱታል ÷
ከእኔም ፡ ሌላ ፡ አይደለም ።
ልቤ ፡ በመናፈቅ ፡ ዝሎአል ።
፳፰፤ በእውነት ፡— እንዴት ፡ እናሳድደዋለን ?
የነገሩ ፡ ሥር ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ተገኝቶአል ፡
ብትሉ ÷
፳፱፤ ፍርድ ፡ እንዳለ ፡ታውቁ ፡ ዘንድ ፡
ቍጣ ፡ የሰይፍን ፡ ቅጣት ፡ ያመጣልና ፡
ከሰይፍ ፡ ፍሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩፤ ናዕማታዊውም ፡ ሶፋር ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡
አለ ፡—
፪፤ ስለዚህ ፡ በውስጤ ፡ ስላለው ፡ ችኰላ ፡ አሳቤ ፡
ትመልስልኛለች ።
፫፤ የሚያሳፍረኝንም ፡ ተግሣጽ ፡ሰምቻለሁ ÷
የማስተዋሌም ፡ መንፈስ ፡ ይመልስልኛል ።
፬፤ ሰው ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ከተቀመጠ ÷ ከዱሮ ፡
ዘመን ፡ጀምሮ ÷
፭፤ የኃጢአተኛ ፡ ፉከራ ፡ አጭር ፡ መሆኑን ፡
የዝንጉዎችም ፡ ደስታ ፡ ቅጽበት ፡ መሆኑን ፡
አታውቁምን ?
፮፤ ከፍታው ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ቢወጣ ÷
ራሱም ፡ እስከ ፡ ደመና ፡ ቢደርስ ÷
፯፤ እንደ ፡ ፋንድያ ፡ ለዘላለም ፡ ይጠፋል ፤
ያዩትም ፡— ወዴት ፡ነው ? ይላሉ ።
፰፤ እንደ ፡ ሕልም ፡ ይበርራል ÷ እርሱም ፡ አይገኝም ፤
እንደ ፡ ሌሊትም ፡ ራእይ ፡ ይሰደዳል ።
፱፤ ያየችውም ፡ ዓይን ፡ ዳግመኛ ፡ አታየውም ፤
ስፍራውም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አይመለከተ
ውም ።
፲፤ ልጆቹ ፡ ድሆቹን ፡ ያቈላምጣሉ ፤
እጁ ፡ ሀብቱን ፡ ይመልሳል ።
፲፩፤ አጥንቶቹ ፡ ብላቴንነቱን ፡ ሞልተዋል ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በመሬት ፡ ውስጥ ፡
ይተኛል ።

፲፪፤ ክፉት ፡ በአፉ ፡ ውስጥ ፡ ቢጣፍጥ ÷
ከምላሱም ፡ በታች ፡ ቢሰውረው ÷
፲፫፤ ቢጠብቀውም ፡ ባይተወውም ÷
በጕሮሮውም ፡ ቢይዘው ÷
፲፬፤ መብሉ ፡ በአንጀቱ ፡ ውስጥ ፡ ይገላበጣል ፤
እንደ ፡ እፉኝትም ፡ ሐሞት ፡ በውስጡ ፡ ይሆናል ።
፲፭፤ የዋጠውን ፡ ሀብት ፡ ይተፋዋል ፤
እግዚአብሔርም ፡ ከሆዱ ፡ ውስጥ ፡ ያወጣዋል ።
፲፮፤ የእፉኝትን ፡ መርዝ ፡ ይጠባል ፤
የእባብም ፡ ምላስ ፡ ይገድለዋል ።
፲፯፤ የማሩንና ፡ የቅቤውን ፡ ፈሳሽ ፡
ወንዞቹንም ፡ አይመለከትም ።
፲፰፤ የድካሙን ፡ ፍሬ ፡ ሳይውጠው ፡ ይመልሰዋል ፤
እንደ ፡ ንግዱም ፡ ትርፍ ፡ አይደሰትም ።
፲፱፤ ድሀውን ፡ አስጨንቆአል ÷ ትቶታልም ፤
ያልሠራውንም ፡ ቤት ፡ በዝብዞአል ።

፳፤ ሆዱ ፡ ዕረፍትን ፡ አላወቀምና ፡
የወደደው ፡ ነገር ፡ አላዳነውም ።
፳፩፤ እርሱ ፡ ከበላ ፡ በኋላ ፡ ምንም ፡ አልተረፈም ፤
ስለዚህ ፡ በረከቱ ፡ አይከናወንለትም ።
፳፪፤ በጠገበ ፡ ጊዜ ፡ ይጨነቃል ፤
የችግረኞችም ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ ታገኘዋለች ።
፳፫፤ ሆዱን ፡ ሳያጠግብ ፡
እግዚአብሔር ፡ የቍጣውን ፡ ትኵሳት ፡ ይሰድ
ድበታል ÷
ሲበላም ፡ ያዘንብበታል ።
፳፬፤ ከብረት ፡ መሣርያም ፡ ይሸሻል ÷
የናስም ፡ ቀስት ፡ ይወጋዋል ።
፳፭፤ እርሱም ፡ ይመዝዘዋል ÷ ከሥጋውም ፡ ይወጣል ፤
ከሐሞቱም ፡ ብልጭ ፡ ብሎ ፡ ይሠርጻል ፤
ፍርሃትም ፡ ይወድቅበታል ።
፳፮፤ ጨለማ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ከበረው ፡ ዕቃ ፡ ተዘጋጅ
ቶአል ፤
በሰው ፡ አፍ ፡ እፍ ፡ የማትባል ፡ እሳት ፡ ትበላ
ዋለች ፤
በድንኳኑ ፡ ውስጥ ፡ የቀረው ፡ ይጨነቅበታል ።
፳፯፤ ሰማይ ፡ ኃጢአቱን ፡ ይገልጥበታል ÷
ምድርም ፡ ትነሣበታለች ።
፳፰፤ የቤቱም ፡ ባለጠግነት ፡ ይሄዳል ፤
በቍጣው ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ፈሳሽ ፡ ውኃ ፡ ያልፋል ።

፳፱፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የበደለኛ ፡ ሰው ፡ እድል ፡ ፈንታ ፥
ከእግዚአብሔርም ፡ የተመደበ ፡ ርስቱ ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩፡ ኢዮብም ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—
፪፡ ስሙ ፥ ቃሌን ፡ ስሙ ፤
ይህም ፡ መጽናናታችሁ ፡ ይሁን ።
፫፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ ተዉኝ ፤
ከተናገርሁም ፡ በኋላ ፡ ተሳለቁ ።
፬፡ በውኑ ፡ የኀዘን ፡ እንጕርጕሮዬ ፡ ለሰው ፡ እናገራለሁን ?
አለመታገሥ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አይገባኝም ?
፭፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ተመልከቱ ፥ ተደነቁም ፤
እጃችሁንም ፡ በአፋችሁ ፡ ላይ ፡ አኑሩ ።
፮፡ እኔ ፡ ባሰብሁ ፡ ቍጥር ፡ እጨነቃለሁ ፥
ፃዕርም ፡ ሥጋዬን ፡ ይይዛል ።
፯፡ ስለ ፡ ምን ፡ ኃጢአተኞች ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉ ?
ስለ ፡ ምንስ ፡ ያረጃሉ ? በባለጠግነትስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይበረታሉ ?
፰፡ ዘራቸው ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፥
ልጆቻቸውም ፡ በዓይናቸው ፡ ፊት ፡ ናቸው ።
፱፡ ቤታቸው ፡ ከፍርሃት ፡ ወጥቶ ፡ የታመነ ፡ ነው ፥
የእግዚአብሔርም ፡ በትር ፡ የለባቸውም ።
፲፡ ኮርማቸው ፡ ይወልዳል ፥ ዘሩንም ፡ አይጥለውም ፤
ላማቸውም ፡ ትወልዳለች ፥ አትጨነግፍም ።
፲፩፡ ሕፃናቶቻቸውን ፡ እንደ ፡ መንጋ ፡ ያወጣሉ ፥
ልጆቻቸውም ፡ ይዘፍናሉ ።
፲፪፡ ከበሮና ፡ መሰንቆ ፡ ወስደው ፡ ይዘምራሉ ፥
በእምቢልታ ፡ ድምፅ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፲፫፡ ዕድሜያቸውንም ፡ በተድላ ፡ ይፈጽማሉ ፤
ድንገትም ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ይወርዳሉ ።
፲፬፡ እግዚአብሔርንም ፡— ከእኛ ፡ ዘንድ ፡ ራቅ ፤
መንገድህን ፡ እናውቅ ፡ ዘንድ ፡ አንወድድም ።
፲፭፡ እናመልከውስ ፡ ዘንድ ፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ አምላክ ፡ ማን ፡ ነው ?
ወይስ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ብንጸልይ ፡ ምን ፡ ይጠቅመናል ? ይላሉ ።
፲፮፡ እነሆ ፥ ሀብታቸው ፡ በእጃቸው ፡ ውስጥ ፡ አይደለምን ?
የኃጥአን ፡ ምክር ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ የራቀች ፡ ናት ።

፲፯፡ የኃጥአን ፡ መብራት ፡ የጠፋው ፥
መቅሠፍትም ፡ የመጣባቸው ፥
እግዚአብሔርም ፡ በቍጣው ፡ መከራ ፡ የከፈላቸው ፥
፲፰፡ በነፋስ ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ገለባ ፥
ዐውሎ ፡ ነፋስም ፡ እንደሚወስደው ፡ ትቢያ ፡ የሆኑ ፡ ስንት ፡ ጊዜ ፡ ነው ?
፲፱፡ እናንተ ፡— እግዚአብሔር ፡ በደላቸውን ፡ ለልጆቻቸው ፡ ይጠብቃል ፡ ብላችኋል ።
እነርሱ ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ ፍዳን ፡ ለራሳቸው ፡ ይክፈል ።
፳፡ ዓይኖቻቸው ፡ ጥፋታቸውን ፡ ይዩ ፥
ሁሉን ፡ ከሚችል ፡ አምላክ ፡ ቍጣ ፡ ይጠጡ ።
፳፩፡ የወራታቸውስ ፡ ቍጥር ፡ ቢቈረጥ ፥
ከእነርሱ ፡ በኋላ ፡ የቤታቸው ፡ ደስታ ፡ ምን ፡ ይሆናቸዋል ?
፳፪፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በሉትስ ፡ ላይ ፡ ለሚፈርድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
በውኑ ፡ ሰው ፡ እውቀትን ፡ ያስተምራልን ?
፳፫፡ አንድ ፡ ሰው ፡ በሰላም ፡ ተዘልሎ ፡ ሲቀመጥ ፡
በሙሉ ፡ ኃይሉ ፡ ሳለ ፡ ይሞታል ።
፳፬፡ በአንጀቱ ፡ ውስጥ ፡ ስብ ፡ ሞልቶአል ፥
የአጥንቶቹም ፡ ቅልጥም ፡ ረጥቦአል ።
፳፭፡ ሌላውም ፡ ሰው ፡ መልካምን ፡ ነገር ፡ ከቶ ፡ ሳይቀምስ ፡
በተመረረች ፡ ነፍስ ፡ ይሞታል ።
፳፮፡ በአፈር ፡ ውስጥ ፡ በአንድ ፡ ላይ ፡ ይተኛሉ ፥
ትልም ፡ ይከድናቸዋል ።

፳፯፡ እነሆ ፥ አሳባችሁን ፥
የመከራችሁብኝንም ፡ ክፉ ፡ ምክር ፡ አውቄአለሁ ።
፳፰፡ እናንተ ፡— የከበርቴው ፡ ቤት ፡ የት ፡ ነው ?
ኃጢአተኛውም ፡ ያደረበት ፡ ድንኳን ፡ የት ፡ ነው ? ብላችኋል ።
፳፱፡ መንገድ ፡ አላፊዎችን ፡ አልጠየቃችሁምን ?
ምልክታቸውን ፡ አታውቁምን ?
፴፡ ኃጢአተኛው ፡ በመቅሠፍት ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ተጠበቀ ፥
በቍጣው ፡ ቀን ፡ እንደሚድን ።
፴፩፡ መንገዱን ፡ በፊቱ ፡ የሚናገር ፡ ማን ፡ ነው ?
የሠራውንስ ፡ የሚመልስበት ፡ ማን ፡ ነው ?
፴፪፡ እርሱን ፡ ግን ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ይሸከሙታል ፥
ሰዎቹም ፡ በመቃብሩ ፡ ላይ ፡ ይጠብቃሉ ።
፴፫፡ የሸለቆው ፡ ጓል ፡ ይጣፍጥለታል ፤
በኋላውም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ይሳበል ፥
በፊቱም ፡ ቍጥር ፡ የሌለው ፡ ጉባኤ ፡ አለ ።
፴፬፡ የምትመልሱልኝ ፡ ውሸትና ፡ ነውና ፡
በከንቱ ፡ እንዴት ፡ ታጽናኑኛላችሁ ?

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩፡ ቴማናዊውም ፡ ኤልፋዝ ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—
፪፡ በውኑ ፡ ሰው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይጠቅመዋልን?
በእውነት ፡ ጥበበኛ ፡ ሰው ፡ ራሱን ፡ ይጠቅማል ።
፫፡ ጻድቅ ፡ መሆንህስ ፡ ሁሉን ፡ የሚችለውን ፡ አምላክ ፡ ደስ ፡ ያሰኘዋልን ?
መንገድህን ፡ ማቅናትህስ ፡ ይጠቅመዋልን ?
፬፡ እርሱንስ ፡ ስለ ፡ ፈራህ ፡ ይዘልፍሃልን ?
ወደ ፡ ፍርድስ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይገባልን ?
፭፡ ክፋትህስ ፡ የበዛ ፡ አይደለምን ?
ለኃጢአትህም ፡ ፍጻሜ ፡ የላትም ።
፮፡ የወንድሞችህን ፡ መያዣ ፡ በከንቱ ፡ ወስደሃል ፥

የእርዘኞቹንም ፡ ልብስ ፡ ዘርፈሃል ።
፯፡ ለደከማ ፡ ውኃ ፡ አላጠጣህም ÷
ለራብተኛም ፡ እንጀራን ፡ ከልክለሃል ።
፰፡ በክንድ ፡ የበረታ ፡ ምድርን ፡ ገዛ ፤
ከበርቴውም ፡ ሰው ፡ ተቀመጠባት ።
፱፡ መበለቲቱን ፡ አንዳች ፡ አልባ ፡ ሰድደሃታል ፤
የድሀ ፡ አደጎችም ፡ ክንድ ፡ ተሰብሮአል ።
፲፡ ስለዚህ ፡ አሽክላ ፡ ከብበሃል ÷
ድንገተኛ ፡ ፍርሃትም ፡ አናውጦሃል ።
፲፩፡ እንዳታይ ፡ ብርሃን ፡ ጨለማ ፡ ሆነችብህ ÷
የውኆችም ፡ ብዛት ፡ አሰጠመህ ።
፲፪፡ እግዚአብሔር ፡ በሰማያት ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አይልምን ?
ከዋክብትም ፡ እንዴት ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እንዳሉ ፡ ተመልከት ።
፲፫፡ አንተም ፡— እግዚአብሔር ፡ ምን ፡ ያውቃል ?
በድቅድቅ ፡ ጨለማ ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ ሊፈርድ ፡ ይችላልን ?
፲፬፡ እንዳያይ ፡ የጠቈረ ፡ ደመና ፡ ጋርዶታል ፤
በሰማይ ፡ ክበብ ፡ ላይ ፡ ይራመዳል ፡ ብለሃል ።
፲፭፡ በውኑ ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ የረገጡአትን ፡
የዱሮይቱን ፡ መንገድ ፡ ትጠብቃለህን ?
፲፮፡ ጊዜያቸው ፡ ሳይደርስ ፡ ተነጠቁ ፤
መሠረታቸውም ፡ እንደ ፡ ፈሳሽ ፡ ውኃ ፡ ፈሰሰ ።
፲፯፡ እግዚአብሔርንም ፡— ከእኛ ፡ ዘንድ ፡ ራቅ ፤
ሁሉንም ፡ የሚችል ፡ አምላክ ፡ ምን ፡ ሊያደርግልን ፡ ይችላል ? አሉት ።
፲፰፡ ነገር ፡ ግን ፡ ቤታቸውን ፡ በመልካም ፡ ነገር ፡ ሞላ ፤
የኃጥአን ፡ ምክር ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ የራቀች ፡ ናት ።
፲፱፡ ጻድቃን ፡ ያዩታል ÷ ደስም ፡ ይላቸዋል ፤
ንጹሐንም ፡ በንቀት ፡ ይስቁበቸዋል ።
፳፡ በእውነት ፡ ሀብታቸው ፡ ጠፋ ÷
የቀረውንም ፡ እሳት ፡ በላች ።

፳፩፡ አሁንም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተስማማ ÷ ሰላምም ፡ ይኑርህ ፤
በዚያም ፡ በጎነት ፡ ታገኛለህ ።
፳፪፡ ከአፉም ፡ ሕጉን ፡ ተቀበል ÷
በልብህም ፡ ቃሉን ፡ አኑር ፤
፳፫፡ ሁሉን ፡ ወደሚችል ፡ አምላክ ፡ ብትመለስ ÷ ብትዋረድም ÷
ኃጢአትንም ፡ ከድንኳንህ ፡ ብታርቅ ÷
፳፬፡ የወርቅን ፡ ዕቃ ፡ በአፈር ፡ ውስጥ ÷
የኦፊርንም ፡ ወርቅ ፡ በጅረት ፡ ድንጋይ ፡ መካከል ፡ ብትጥል ÷
፳፭፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ አምላክ ፡ ወርቅና ፡ የሚብለጨለጭ ፡ ብር ፡ ይሆንልሃል ።
፳፮፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሁሉን ፡ በሚችል ፡ አምላክ ፡ ደስ ፡ ይልሃል ÷
ፊትህንም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ታነሣለህ ።
፳፯፡ ወደ ፡ እርሱም ፡ ትጸልያለህ ÷ እርሱም ፡ ይሰማሃል ፤
ስእለትህንም ፡ ትሰጣለህ ።
፳፰፡ ነገርንም ፡ ትመክራለህ ÷ እርሱም ፡ ይሰክልሃል ፤
ብርሃንም ፡ በመንገድህ ፡ ላይ ፡ ይበራል ።
፳፱፡ ቢያዋርዱህ ፡ አንተ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ትላለህ ፤
ትሑቱንም ፡ ሰው ፡ ያድነዋል ።
፴፡ ንጹሑን ፡ ሰው ፡ ያድነዋል ፤
በእጅህም ፡ ንጽሕና ፡ ትድናለህ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩፡ ኢዮብም ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—
፪፡ ዛሬም ፡ ደግሞ ፡ የኀዘን ፡ እንጕርጕሮዬ ፡ ገና ፡ መራራ ፡ ነው ፤
እጁ ፡ በልቅሶ ፡ ጩኸቴ ፡ ላይ ፡ ከብዳለች ።
፫፡ እርሱን ፡ ወዴት ፡ እንዳገኘው ፡ ምነው ፡ በወቅሁ !
ወደ ፡ ተቀመጠበትስ ፡ ስፍራ ፡ ምነው ፡ በደረስሁ !
፬፡ በፊቱ ፡ ሙግቴን ፡ አዘጋጅ ፡ ነበር ÷
አፌንም ፡ በማስረጃ ፡ እሞላው ፡ ነበር ።
፭፡ የሚመልስልኝም ፡ ቃል ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አውቅ ፡ ነበር ÷
የሚለኝንም ፡ አስተውል ፡ ነበር ።
፮፡ በኃይሉ ፡ ብዛት ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ይምዋገት ፡ ነበርን ?
እንኳን ! ያደምጠኝ ፡ ነበር ።
፯፡ ቅን ፡ ሰው ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በዚያ ፡ ይከራከር ፡ ነበር ፤
እኔም ፡ ከፈራጄ ፡ ለዘላለም ፡ እድን ፡ ነበር ።
፰፡ እነሆ ÷ ወደ ፡ ፊት ፡ እሄዳለሁ ÷ እርሱም ፡ የለም ፤
ወደ ፡ ኋላም ፡ እሄዳለሁ ÷ እኔም ፡ አላስተውለውም ፤
፱፡ ወደሚሠራበት ፡ ወደ ፡ ግራ ፡ ብሄድ ፡ አልመለከተውም ፤
በቀኝም ፡ ይሰወራል ÷ አላየውምም ፤

፲፡ የምሄድበትን ፡ መንገድ ፡ ያውቃል ፤
ከፈተነኝም ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ወርቅ ፡ እወጣለሁ ።
፲፩፡ እግሬ ፡ ወደ ፡ እርምጃው ፡ ተጣብቆአል ፤
መንገዱንም ፡ ጠብቄአለሁ ÷ ፈቀቅም ፡ አላልሁም ።
፲፪፡ ከከንፈሩ ፡ ትእዛዝ ፡ አልተመለስሁም ፤
የአፉን ፡ ቃል ፡ በልቤ ፡ ሰውሬአለሁ ።
፲፫፡ እርሱ ፡ ግን ፡ ብቻውን ፡ ነው ፤ እርሱንስ ፡ የሚመስለው ፡ ማን ፡ ነው ?
ነፍሱም ፡ የወደደችውን ፡ ያደርጋል ።
፲፬፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ የተወሰነውን ፡ ይፈጽማል ፤
እንደዚህም ፡ ያለ ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ አለ ።
፲፭፡ ስለዚህ ፡ በፊቱ ፡ ደነገጥሁ ፤
በሰብሁም ፡ ጊዜ ፡ ከእርሱ ፡ ፈራሁ ።
፲፮፡ እግዚአብሔር ፡ ልቤን ፡ አባብቶታልና ÷
ሁሉንም ፡ የሚችል ፡ አምላክ ፡ አስደንግጦኛል ።
፲፯፡ ከጨለማው ፡ የተነሣ ÷
ድቅድቁም ፡ ጨለማ ፡ ፊቴን ፡ ከመከደኑ ፡ የተነሣ ፡ አልደነገጥሁም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩፡ ሁሉን ፡ ከሚችል ፡ አምላክ ፡ ዘንድ ፡ ዘመናት ፡ አልተሰወረምና ፡
እርሱን ፡ የሚያውቁ ፡ ለምን ፡ ወራቱን ፡ አያዩም ?

፪፤ የድንበሩን ፡ ምልክት ፡ የሚያፈርሱ ፡ አሉ ፤
መንጋዎቹን ፡ በዝብዘው ፡ ያሰማራሉ ።
፫፤ የድሀ ፡ አድጎቹን ፡ አሀያ ፡ ይነዳሉ ፤
የመበለቲቱን ፡ በሬ ፡ ስለ ፡ መያዣ ፡ ይወስዳሉ ።
፬፤ ድሆቹን ፡ ከመንገድ ፡ ያወጣሉ ፤
የምድርም ፡ ችግረኞች ፡ ሁሉ ፡ ይሸሸጋሉ ።
፭፤ እነሆ ÷ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንዳሉ ፡ እንደ ፡ ሜዳ ፡ አህዮች ÷
መብልን ፡ ፈልገው ፡ ወደ ፡ ሥራቸው ፡ ይወጣሉ ፤
ምድረ ፡ በዳውም ፡ ለልጆቻቸው ፡ መብልን ፡ ይሰጣቸዋል ።
፮፤ እነዚያ ፡ በእርሻ ፡ ውስጥ ፡ እህላቸውን ፡ ያጭዳሉ ፤
የበደለኛውንም ፡ ወይን ፡ ይቃርማሉ ።
፯፤ ራቁታቸውን ፡ ያለ ፡ ልብስ ፡ ያድራሉ ÷
በብርድ ፡ ጊዜ ፡ መጐናጸፊያ ፡ የላቸውም ።
፰፤ ከተራሮች ፡ በሚወርድ ፡ ዝናብ ፡ ይረጥባሉ ፤
መጠጊያም ፡ አጥተው ፡ ቋጥኙን ፡ ያቅፋሉ ።
፱፤ ድሀ ፡ አደጉን ፡ ልጅ ፡ ከጡቱ ፡ የሚነጥሉ ፡ አሉ ፤
ከችግረኛውም ፡ መያዣ ፡ ይወስዳሉ ።
፲፤ ያለ ፡ ልብስ ፡ ራቁታቸውን ፡ ይሄዳሉ ፤
ተርበውም ፡ ነዶዎችን ፡ ይሸከማሉ ፤
፲፩፤ በእነዚህ ፡ ሰዎች ፡ አጥር ፡ ውስጥ ፡ ዘይት ፡ ያደርጋሉ ፤
ወይንም ፡ ይጠምቃሉ ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ይጠማሉ ።
፲፪፤ ከከተማውና ፡ ከገዛ ፡ ቤቶቻቸው ፡ ይባረራሉ ፤
የልጆችም ፡ ነፍስ ፡ ለእርዳታ ፡ ትጮኻለች ፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ስንፍናቸውን ፡ አይመለከትም ።

፲፫፤ እነዚህ ፡ በብርሃን ፡ ላይ ፡ የሚያምፁ ፡ ናቸው ፤
መንገዱን ፡ አያውቁም ÷ በጎዳናውም ፡ አይጸኑም ።
፲፬፤ ነፍሰ ፡ ገዳዩም ፡ ሳይነጋ ፡ ማልዶ ፡ ይነሣል ፤
ችግረኞችንና ፡ ድሆችን ፡ ይገድላል ፤
በሌሊትም ፡ እንደ ፡ ሌባ ፡ ነው ።
፲፭፤ የአመንዝራም ፡ ዓይን ፡ ድግዝግዝታን ፡ ይጠብቃል ፡—
የማንም ፡ ዓይን ፡ አያየኝም ፡ ይላል ÷
ፊቱንም ፡ ይሸፍናል ።
፲፮፤ ቤቶቹን ፡ በጨለማ ፡ ይነድላሉ ፤
በቀን ፡ ይሸሸጋሉ ፤
ብርሃንም ፡ አያውቁም ።
፲፯፤ የጥዋት ፡ ብርሃን ፡ ለእነርሱ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሞት ፡ ጥላ ፡ ነው ፤
የሞትን ፡ ጥላ ፡ ድንጋጤ ፡ ያውቃሉና ።

፲፰፤ እነርሱ ፡ በውኃ ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ በርረው ፡ ያልፋሉ ፤
እድል ፡ ፈንታቸውም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የተረገመች ፡ ናት ፤
ወደ ፡ ወይኑ ፡ በታ ፡ መንገድ ፡ አይዞሩም ።
፲፱፤ ድርቅና ፡ ሙቀት ፡ የአመዳዩን ፡ ውኃ ፡ ያጠፋሉ ፤
እንዲሁ ፡ ሲኦል ፡ በደለኞችን ፡ ታጠፋለች ።
፳፤ ማኅፀን ፡ ትረሳዋለች ፤
ትልም ፡ በደስታ ፡ ይጠባዋል ፤
ዳግመኛም ፡ አይታሰብም ፤
ክፋትም ፡ እንደ ፡ ዛፍ ፡ ይሰበራል ።
፳፩፤ የማትወልደውን ፡ መካኒቱን ፡ ይበድላታል ፤
ለመበለቲቱም ፡ በጎነት ፡ አያደርግም ።
፳፪፤ ነገር ፡ ግን ፡ በኃይሉ ፡ ኃያላንን ፡ ይስባል ፤
እርሱም ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ ሰው ፡ በሕይወቱ ፡ አይታመንም ።
፳፫፤ እግዚአብሔር ፡ በደኅና ፡ አኑሮአቸዋል ÷
በዚያም ፡ ይታመናሉ ፤
ዓይኖቹ ፡ ግን ፡ በመንገዳቸው ፡ ላይ ፡ ናቸው ።
፳፬፤ ጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላሉ ፤
ይሄዳሉ ÷ ይጠወልጋሉም ፤
እንደ ፡ ሌሎች ፡ ሁሉ ፡ ይከማቻሉ ፤
እንደ ፡ እሸትም ፡ ራስ ፡ ይቈረጣሉ ።
፳፭፤ እንዲህስ ፡ ባይሆን ፡ ሐሰተኛ ፡ የሚያደርገኝ ÷
ነገሬንስ ፡ እንደ ፡ ምናምን ፡ የሚያደርገው ፡ ማን ፡ ነው ?

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

፩፤ ሹሐዊውም ፡ በልዳዶስ ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—
፪፤ ገዢነትና ፡ መፈራት ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ናቸው ፤
በከፍታውም ፡ ሰላም ፡ አድራጊ ፡ ነው ።
፫፤ በውኑ ፡ ለሠራዊቶቹ ፡ ቍጥር ፡ አላቸውን ?
ብርሃኑስ ፡ የማይወጣው ፡ በማን ፡ ላይ ፡ ነው ?
፬፤ ሰውስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ጻድቅ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ÷
ከሴትስ ፡ የተወለደ ፡ ንጹሕ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ይችላል ?
፭፤ እነሆ ÷ ጨረቃ ፡ እንኳ ፡ ብሩህ ፡ አይደለም ÷
ከዋክብትም ፡ በፊቱ ፡ ንጹሐን ፡ አይደሉም ።
፮፤ ይልቁንስ ፡ ብስብስ ፡ የሆነ ፡ ሰው ÷
ትልም ፡ የሆነ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ምንኛ ፡ ያንስ !

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩፤ ኢዮብም ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—
፪፤ ኃይል ፡ የሌለውን ፡ ምንኛ ፡ ረዳኸው !
ብርታት ፡ የሌለውን ፡ ክንድ ፡ ምንኛ ፡ አዳንኸው !
፫፤ ጥበብስ ፡ የሌለውን ፡ ምንኛ ፡ መከርኸው !
ብዙ ፡ እውቀትንስ ፡ ምንኛ ፡ ገለጥህለት !
፬፤ ይህንስ ፡ ቃል ፡ በማን ፡ እርዳታ ፡ ተናገርህ ?
የማንስ ፡ መንፈስ ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ?

፭፤ ሙታን ፡ ሰዎች ፡ ከውኆች ፡ በታች ÷
በውኆችም ፡ ውስጥ ፡ ከሚኖሩ ፡ በታች ፡ ይንቀጠቀጣሉ ።
፮፤ ሲኦል ፡ በፊቱ ፡ ራቁትዋን ፡ ናት ÷
ለጥፋትም ፡ መጋረጃ ፡ የለውም ።
፯፤ ሰሜንን ፡ በባዶ ፡ስፍራ ፡ ላይ ፡ ይዘረጋል ÷
ምድሪቱንም ፡ በታችዋ ፡ አንዳች ፡ አልባ ፡ ያንጠለጥላል ።
፰፤ ውኆችን ፡ በደመናዎቹ ፡ ውስጥ ፡ ያስራል ÷
ደመናይቱም ፡ ከታች ፡ አልተቀደደችም ።

፱፤ የዙፋኑን ፡ ፊት ፡ ይከድናል ÷
ደመናውንም ፡ ይዘረጋበታል ።
፲፤ ብርሃንና ፡ ጨለማ ፡ እስከሚለያዩበት ፡ ዳርቻ ፡
ድረስ ÷
በውኆች ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ ድንበርን ፡ አደረገ ።
፲፩፤ የሰማይ ፡ አዕማድ ፡ ይንቀጠቀጣሉ ÷
ከተግሣጹም ፡ የተነሣ ፡ ይደነግጣሉ ።
፲፪፤ በኃይሉ ፡ ባሕርን ፡ ጸጥ ፡ ያደርጋል ÷
በማስተዋሉም ፡ ረዓብን ፡ ይመታል ።
፲፫፤ በመንፈሱ ፡ ሰማያት ፡ ውበትን ፡ አገኙ ÷
እጁም ፡ በራሪይቱን ፡ እባብ ፡ ወጋች ።
፲፬፤ እነሆ ÷ ይህ ፡ የመንገዱ ፡ ዳርቻ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤
ይህም ፡ የሰማነው ፡ ነገር ፡ ምንኛ ፡ ጥቂት ፡ ነው !
የኃይሉንስ ፡ ነጐድጓድ ፡ ያስተውል ፡ ዘንድ ፡
ማን ፡ ይችላል ?

ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

፩፤ ኢዮብም ፡ ምሳሌውን ፡ ይመስል ፡ ዘንድ ፡
ደገመ ÷ እንዲህም ፡ አለ ፡—
፪፤ ፍርዴን ፡ ያስወገደ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን !
ነፍሴንም ፡ መራራ ፡ ያደረገ ፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡
ሕያው ፡ አምላክን !
፫፤ እስትንፋሴ ፡ በእኔ ፡ ውስጥ ÷
የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በአፍንጫዬ ፡
ውስጥ ፡ ገና ፡ ሳለ ÷
፬፤ ከንፈሬ ፡ ኃጢአትን ፡ አትናገርም ÷
አንደበቴም ፡ሽንገላን ፡ አያወጣም ።
፭፤ እናንተን ፡ ማጽደቅ ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ይራቅ ፤
እስከሞት ፡ ድረስ ፡ ፍጹምነቴን ፡ ከእኔ ፡ አላር
ቅም ።
፮፤ ጽድቄን ፡ እይዛለሁ ፡ እርሱንም ፡ አልተውም ፤
ከቀኖቼም ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ አንዱ ፡ ልቤ ፡ አይዘል
ፈኝም ።

፯፤ ጠላቴ ፡ እንደ ፡ በደለኛ ÷
በእኔ ፡ ላይም ፡ የሚነሣ ፡ እንደ ፡ ኃጢአተኛ ፡
ይሁን ።
፰፤ እግዚአብሔር ፡ ባጠፋውና ፡ ነፍሱን ፡ በለየ ፡ ጊዜ ÷
የዝንጉ ፡ ሰው ፡ ተስፋው ፡ ምንድር ፡ ነው ?
፱፤ በውኑ ፡ መከራ ፡ በመጣበት ፡ ጊዜ ÷
እግዚአብሔር ፡ ጩኸቱን ፡ ይሰማልን ?
፲፤ ሁሉንስ ፡ በሚችል ፡ አምላክ ፡ ደስ ፡ ይለዋልን ?
እግዚአብሔርንስ ፡ ሁልጊዜ ፡ ይጠራልን ?
፲፩፤ እኔ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ አስተምራች
ኋለሁ ፤
ሁሉን ፡ በሚችል ፡ አምላክ ፡ ዘንድ ፡ ያለውን ፡
አልሸሽግም ።
፲፪፤ እነሆ ÷ ሁላችሁ ፡ አይታችኋል ፤
ስለ ፡ ምን ፡ ከንቱ ፡ ሆናችሁ ?

፲፫፤ ይህች ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የበደለኛ ፡
እድል ፡ ፈንታ ÷
ግፈኛም ፡ ሁሉን ፡ ከሚችል ፡ አምላክ ፡ ዘንድ ፡
የሚቀበላት ፡ ርስት ፡ ናት ፤
ልጆቹ ፡ ቢበዙ ፡ ለሰይፍ ፡ ይሆናሉ ፤ ፲፬፤
ዘሩም ፡ እንጀራን ፡ አይጠግብም ።
ለእርሱም ፡ የቀሩት ፡ በቸነፈር ፡ ይቀበራሉ ፤ ፲፭፤
መበለቶቻቸውም ፡ አያለቅሱም ።
እርሱ ፡ ብርን ፡ እንደ ፡ አፈር ፡ ቢከምር ÷ ፲፮፤
ልብስንም ፡ እንደ ፡ ጭቃ ፡ ቢያዘጋጅ ÷
እርሱ ፡ ያዘጋጀው ፡ ይሆናል ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ፲፯፤
ጻድቅ ፡ ይለብሰዋል ፤
ብሩንም ፡ ንጹሐን ፡ ይከፋፈሉታል ።
የሚሠራው ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ሸረሪት ፡ ድር ፡ ፲፰፤
ይሠራል ÷
ጠባቂም ፡ እንደሚሠራው ፡ ጎጆ ፡ ነው ።
ባለጠጋ ፡ ሆኖ ፡ ይተኛል ÷ ዳግመኛም ፡ አይተኛም ፤ ፲፱፤
ዓይኑን ፡ ይከፍታል ÷ እርሱም ፡ የለም ።
ድንጋጤ ፡ እንደ ፡ ጐርፍ ፡ ታገኘዋለች ፤ ፳፤
በሌሊትም ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ትነጥቀዋለች ።
የምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ ያነሣዋል ÷ እርሱም ፡ ይሄዳል ፤ ፳፩፤
ከበታውም ፡ ይጠርገዋል ።
እርሱ ፡ ይጥልበታል ÷ አይራራለትም ፤ ፳፪፤
ከእጁም ፡ ፈጥኖ ፡ መሸሽ ፡ ይወድዳል ።
ሰው ፡ በእጁ ፡ ያጨበጭብበታል ፤ ፳፫፤
ከስፍራውም ፡ በፉጨት ፡ ያስወጡታል ።

ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

በእውነት ፡ ብር ፡ የሚወጣበት ÷ ፩፤
ወርቅም ፡ የሚነጠርበት ፡ ስፍራ ፡ አለ ።
ብረት ፡ ከመሬት ፡ ውስጥ ፡ ይወሰዳል ፤ ፪፤
መዳብም ፡ ከድንጋይ ፡ ይቀለጣል ።
ሰው ፡ ለጨለማ ፡ ፍጻሜን ፡ ያደርጋል ፤ ፫፤
የጨለማውንና ፡ የሞት ፡ ጥላን ፡ ድንጋይ ፡ እስከ ፡
ወሰኑ ፡ ድረስ ፡ ይፈላልጋል ።
ሰው ፡ ከሚኖርበት ፡ ርቀው ፡ መውረጃ ፡ ይቈ ፬፤
ፍራሉ ፤
ከሰውም ፡ እግር ፡ ተረሱ ÷
ከሰዎችም ፡ ርቀው ፡ እየተንጠለጠሉ ፡ ይወዛወ
ዛሉ ።
እንጀራ ፡ ከምድር ፡ ውስጥ ፡ ይወጣል ፤ ፭፤
በእሳትም ፡ እንደሚሆን ፡ ታችኛው ፡ ይገለበ
ጣል ።
ድንጋይዋ ፡ የሰንፔር ፡ ስፍራ ፡ ነው ÷ ፮፤
የወርቅም ፡ ድቃቂ ፡ አለው ።
መንገድዋን ፡ ጭልፊት ፡ አያውቀውም ÷ ፯፤
የአሞራም ፡ ዓይን ፡ አላየውም ።
የትዕቢት ፡ ልጆች ፡ አልረገጡአትም ÷ ፰፤
ደቦል ፡ አንበሳ ፡ አላለፈባትም ።
ሰው ፡ ወደ ፡ ቡላድ ፡ ድንጋይ ፡ እጁን ፡ ይዘረጋል ÷ ፱፤
ተራራውንም ፡ ከመሠረቱ ፡ ይገለብጣል ።
ከድንጋይ ፡ ውስጥ ፡ መንዶልዶያ ፡ ይወቅራል ፤ ፲፤
ዓይኑም ፡ ዕንቍን ፡ ሁሉ ፡ ታያለች ።
ፈሳሹም ፡ እንዳይንጠባጠብ ፡ ይገድባል ፤ ፲፩፤
የተሰወረውንም ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ብርሃን ፡ ያወጣል ።

ነገር ፡ ግን ፡ ጥበብ ፡ የምትገኘው ፡ ወዴት ፡ ነው ? ፲፪፤
የማስተዋልስ ፡ ስፍራ ፡ ወዴት ፡ ነው ?

፲፫፡ ሰው ፡ መንገድዋን ፡ አያውቅም ፤
በሕያዋን ፡ ምድር ፡ አትገኝም ።
፲፬፡ ቀላይ ፦ በእኔ ፡ ውስጥ ፡ የለችም ፡ ይላል ፤
ባሕርም ፦ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ የለችም ፡ ይላል ።
፲፭፡ በምዝምዝ ፡ ወርቅ ፡ አትገኝም ፥
ብርም ፡ ስለ ፡ ዋጋዋ ፡ አይመዘንም ።
፲፮፡ በኦፊር ፡ ወርቅ ፥
በከበረም ፡ መረግድና ፡ በሰንፔር ፡ አትገመትም ።
፲፯፡ ወርቅና ፡ ብርጭቆ ፡ አይወዳደሩአትም ፥
በጥሩ ፡ ወርቅም ፡ ዕቃ ፡ አትለወጥም ።
፲፰፡ ስለ ፡ ዛጐልና ፡ ስለ ፡ አልማዝ ፡ አይነገርም ።
የጥበብ ፡ ዋጋ ፡ ከቀይ ፡ ዕንቍ ፡ ይልቅ ፡ ይበልጣል ።
፲፱፡ የኢትዮጵያ ፡ ቶጳዝዮን ፡ አይተካከላትም ፥
በጥሩም ፡ ወርቅ ፡ አትገመትም ።
፳፡ እንግዲያስ ፡ ጥበብ ፡ ከወዴት ፡ ትመጣለች ?
የማስተዋልስ ፡ ስፍራ ፡ ወዴት ፡ ነው ?
፳፩፡ ከሕያዋን ፡ ሁሉ ፡ ዓይን ፡ ተሰውራለች ፥
ከሰማይ ፡ ወፎች ፡ ተሸሽጋለች ።
፳፪፡ ጥፋትና ፡ ሞት ፦ ወሬዋን ፡ በጆሮቻችን ፡ ሰማን ፡ ብለዋል ።

፳፫፡ እግዚአብሔር ፡ መንገድዋን ፡ ያስተውላል ፥
እርሱም ፡ ስፍራዋን ፡ ያውቃል ።
፳፬፡ እርሱም ፡ የምድርን ፡ ዳርቻ ፡ ይመለከታል ፥
ከሰማይም ፡ በታች ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ያያል ።
፳፭፡ ለነፋስ ፡ ሚዛንን ፡ ባደረገለት ፡ ጊዜ ፥
ውኆችንም ፡ በስፍር ፡ በሰፈረ ፡ ጊዜ ፥
፳፮፡ ለዝናብም ፡ ሥርዓትን ፥
ለነጐድጓድ ፡ መብረቅም ፡ መንገድን ፡ በደረገ ፡ ጊዜ ፥
፳፯፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አያት ፥ ገለጣትም ፤
አዘጋጃትም ፥ ደግሞም ፡ መረመራት ።
፳፰፡ ሰውንም ፦ እነሆ ፥ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ጥበብ ፡ ነው ፤
ከኃጢአትም ፡ መራቅ ፡ ማስተዋል ፡ ነው ፡ አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

፩፡ ኢዮብም ፡ ምሳሌውን ፡ ይመስል ፡ ዘንድ ፡ ደገመ ፥ እንዲህም ፡ አለ ፦
፪፡ እግዚአብሔር ፡ ይጠብቀኝ ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡ ጊዜ ፥
እንደ ፡ ፊተኛው ፡ ወራት ፡ ምነው ፡ በሆንሁ !
፫፡ በራሴ ፡ ላይ ፡ መብራቱ ፡ በበራ ፡ ጊዜ ፥
እኔም ፡ ጨለማውን ፡ አልፌ ፡ በብርሃኑ ፡ በሄድሁ ፡ ጊዜ ፥
፬፡ በሙሉ ፡ ሰውነቴ ፡ እንደ ፡ ነበርሁ ፡ ጊዜ ፥
እግዚአብሔር ፡ ድንኳኔን ፡ በጋረደ ፡ ጊዜ ፥
፭፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ አምላክ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ገና ፡ ሳለ ፥
ልጆቼም ፡ በዙሪያዬ ፡ ሳሉ ፥
፮፡ መንገዴ ፡ በቅቤ ፡ ይታጠብ ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፥
ድንጋዩ ፡ የዘይት ፡ ፈሳሽ ፡ ያፈስስልኝ ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ።
፯፡ ወደ ፡ ከተማይቱ ፡ በር ፡ በወጣሁ ፡ ጊዜ ፥
በአደባባዩም ፡ ወንበሬን ፡ ባኖርሁ ፡ ጊዜ ፥
፰፡ ጐበዛዝት ፡ እኔን ፡ አይተው ፡ ተሸሸጉ ፥
ሽማግሌዎችም ፡ ተነሥተው ፡ ቆሙ ።
፱፡ አለቆቹ ፡ ከመናገር ፡ ዝም ፡ አሉ ፥
እጃቸውንም ፡ በአፋቸው ፡ ላይ ፡ ጫኑ ።
፲፡ የታላላቆቹም ፡ ድምፅ ፡ አረመመ ፤
ምላሳቸውም ፡ በትናጋቸው ፡ ተጣጋ ።
፲፩፡ የሰማችኝ ፡ ጆሮ ፡ አሞገሰችኝ ፥
ያየችኝም ፡ ዓይን ፡ መሰከረችልኝ ፤
፲፪፡ የሚጮኸውን ፡ ችግረኛ ፥
ድሀ ፡ አደጉንና ፡ ረዳት ፡ የሌለውን ፡ አድኜ ፡ ነበርሁና ።
፲፫፡ ለጥፋት ፡ የቀረበው ፡ በረከት ፡ በላዬ ፡ መጣ ፤
የበልቴቲቱንም ፡ ልብ ፡ እልል ፡ አሰኘሁ ።
፲፬፡ ጽድቅን ፡ ለበስሁ ፡ እርስዋም ፡ ለበሰችኝ ፤
ፍርዴም ፡ እንደ ፡ መጐናጸፊያና ፡ እንደ ፡ ዙፋር ፡ ነበረ ።
፲፭፡ ለዕውር ፡ ዓይን ፥
ለአንካሳ ፡ እግር ፡ ነበርሁ ።
፲፮፡ ለድሀው ፡ አባት ፡ ነበርሁ ፤
የማላውቀውንም ፡ ሰው ፡ሙግት ፡ መረመርሁ ።
፲፯፡ የኃጢአተኛውን ፡ መንጋጋ ፡ ሰበርሁ ፥
የነጠቀውንም ፡ ከጥርሱ ፡ ውስጥ ፡ አስጣልሁ ።
፲፰፡ እኔም ፡ አልሁ ፦ በልጆቼ ፡ መካከል ፡ እሞታለሁ ፥
ዕድሜዬንም ፡ እንደ ፡ አሸዋ ፡ አበዛለሁ ፤
፲፱፡ ሥሬ ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡ ተዘርግቶአል ፥
ጠልም ፡ በቅርንጫፌ ፡ ላይ ፡ ያድራል ፤
፳፡ ክብሬ ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ታድሶአል ፥
ቀስቴም ፡ በእጄ ፡ ውስጥ ፡ ለምልሞአል ።
፳፩፡ ሰዎች ፡ እኔን ፡ ሰምተው ፡ በትዕግሥት ፡ ተጠባበቁ ፥
ምክሬንም ፡ ለማዳመጥ ፡ ዝም ፡ አሉ ።
፳፪፡ ከቃሌ ፡ በኋላ ፡ አንዳች ፡ አልመለሱም ፤
ንግግሬም ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ተንጠባጠበ ።
፳፫፡ ዝናብን ፡ እንደሚጠብቁ ፡ በትዕግሥት ፡ ጠበቁኝ ፤
የጥቢን ፡ ዝናብ ፡ እንደሚሹ ፡ አፋቸውን ፡ ከፈቱ ።
፳፬፡ እነርሱ ፡ ባልታመኑ ፡ ጊዜ ፡ ሳቅሁላቸው ፤
የፊቴንም ፡ ብርሃን ፡ አላወረዱም ።
፳፭፡ መንገዳቸውን ፡ መረጥሁ ፤
እንደ ፡ አለቃ ፡ ሆኜ ፡ ተቀመጥሁ ፤
ንጉሥ ፡ በሠራዊቱ ፡ መካከል ፡ እንደሚኖር ፥
ኀዘንተኞችን ፡ እንደሚያጽናና ፡ ኖርሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

፩፡ አሁን ፡ ግን ፡ በዕድሜ ፡ ከእኔ ፡ የሚያንሱ ፥
አባቶቻቸውን ፡ ከመንጋዬ ፡ ውሾች ፡ ጋር ፡ ለማኖር ፡ የናቅኋቸው ፥
በእኔ ፡ ላይ ፡ ተሳለቁብኝ ።
፪፡ ሙሉ ፡ ሰው ፡ መሆናቸው ፡ ጠፍቶባቸው ፡ ነበርና ፡
የእጃቸው ፡ ብርታት ፡ ለእኔ ፡ ምን ፡ ይጠቅማል ?
፫፡ በራብና ፡ በቀጠና ፡ የመነመኑ ፡ ናቸው ፤

የመፍረስና፡የመፈታት፡ጨለማ፡ወዳለበት፡
ወደ፡ምድረ፡በዳ፡ይሸሻሉ።
፬፡ በቍጥቋጦ፡አጠገብ፡ያለውን፡
ጨው፡ጨው፡የሚለውን፡አትክልት፡ይለቅ
ማሉ፤
የክትክታ፡ሥር፡ደግሞ፡መብላቸው፡ነው።
፭፡ ከሰዎች፡ተለይተው፡ተሰደዱ፤
በሌባ፡ላይ፡እንደሚጮኽ፡ይጮኹባቸዋል።
፮፡ በሸለቆ፡ፈረፈርና፡በምድር፡ጕድጓድ፡
በድንጋይም፡ዋሻ፡ውስጥ፡ይኖራሉ።
፯፡ በቍጥቋጦ፡መካከል፡ይጮኻሉ፤
ከሳማ፡በታች፡ተሰብስበዋል።
፰፡ የሰነፎችና፡የነውረኞች፡ልጆች፡ናቸው፤
ከምድርም፡በግርፋት፡የተባረሩ፡ናቸው።

፱፡ አሁንም፡እኔ፡መዝፈኛና፡መተረቻ፡ሆንኋ
ቸው።
፲፡ ተጸየፉኝ፥ከእኔም፡ራቁ፤
አክታቸውንም፡በፊቴ፡መትፋትን፡አልተ
ዉም።
፲፩፡ የቀስቴን፡አውታር፡አላልቶብኛል፥አዋርዶ
ኝማል፤
እነርሱም፡በፊቴ፡ልጓማቸውን፡ፈትተዋል።
፲፪፡ በቀኜ፡በኩል፡ዱርዬዎች፡ተነሥተዋል፥
እግሬንም፡ይገለብጣሉ፤
የጥፋታቸውን፡መንገድ፡በእኔ፡ላይ፡ይጐድ
ባሉ።
፲፫፡ ጐዳናዬን፡ያበላሻሉ፤
ረዳት፡የሌላቸው፡ሰዎች፡መከራዬን፡ያበዛሉ።
፲፬፡ በሰፊ፡ፍራሽ፡እንደሚመጡ፡ይመጡብኛል፤
በባድማ፡ውስጥ፡ይንከባለሉብኛል።
፲፭፡ ድንጋጤ፡በላዬ፡ተመለሰችብኝ፥
ክብሬንም፡እንደ፡ነፋስ፡ያሳድዱአታል፤
ደኅንነቴም፡እንደ፡ደመና፡አልፋለች።

፲፮፡ አሁንም፡ነፍሴ፡በውስጤ፡ፈሰሰች፤
የመከራም፡ዘመን፡ያዘችኝ።
፲፯፡ በሌሊት፡አጥንቴ፡በደዌ፡ተነደለች፥
ጅማቶቼም፡አያርፉም።
፲፰፡ ከታላቁ፡ደዌ፡ኀይል፡የተነሣ፡ልብሴ፡ተበላ
ሸች፤
እንደ፡ቀሚስ፡ክሳድ፡አነቀችኝ።
፲፱፡ እርሱ፡በጭቃ፡ውስጥ፡ጣለኝ፥
አፈርና፡አመድም፡መሰልሁ።
፳፡ ወደ፡አንተ፡ጮኽሁ፥አልመለስህልኝም፤
ተነሣሁ፥አልተመለከትኸኝም።
፳፩፡ ተመልሰህ፡ጨካኝ፡ሆንህብኝ፤
በእጅህም፡ብርታት፡አስጨነቅኸኝ።
፳፪፡ በነፋስ፡አነሣኸኝ፥በላዩም፡አስቀመጥኸኝ፤
በዐውሎ፡ነፋስ፡አቀለጥኸኝ።
፳፫፡ ለሞት፡ሕያዋንም፡ሁሉ፡ለሚሰበሰቡበት፡ቤት፡
አሳልፈህ፡እንደምትሰጠኝ፡አውቄአለሁና።

፳፬፡ ነገር፡ግን፡ሰው፡በወደቀ፡ጊዜ፡እጁን፡አይ
ዘረጋምን?
በጥፋቱስ፡ጊዜ፡አይጮኽምን?
፳፭፡ ጭንቅ፡ቀን፡ላገኘው፡ሰው፡አላለቀስሁምን?
ለችግረኛስ፡ነፍሴ፡አላዘነችምን?
፳፮፡ ነገር፡ግን፡በጎነትን፡በተጠባበቅሁ፡ጊዜ፡
ክፉ፡ነገር፡መጣችብኝ፤
ብርሃንን፡በትዕግሥት፡ጠበቅሁ፥ጨለማም፡
መጣ።
፳፯፡ አንጀቴ፡ፈላች፥አላረፈችም፤
የመከራም፡ዘመን፡መጣችብኝ።
፳፰፡ ያለ፡ፀሐይ፡በትካዜ፡ሄድሁ፤
በጉባኤም፡መካከል፡ቆሜ፡ጮኽሁ።
፳፱፡ ለቀበሮ፡ወንድም፥
ለሰጐንም፡ባልንጀራ፡ሆንሁ።
፴፡ ቁርበቴ፡ጠቈረ፥ከእኔም፡ተለይቶ፡እርግፍ
ግፍ፡አለ፤
አጥንቴም፡ከትኵሳት፡የተነሣ፡ተቃጠለች።
፴፩፡ ስለዚህ፡መሰንቆዬ፡ለኀዘን፥
እምቢልታዬም፡ለሚያለቅሱ፡ቃል፡ሆነ።

## ምዕራፍ፡፴፩።

፩፡ ከዓይኔ፡ጋር፡ቃል፡ኪዳን፡ገባሁ፤
እንግዲህስ፡ቈንጆይቱን፡እንዴት፡እመለከ
ታለሁ?
፪፡ የእግዚአብሔር፡እድል፡ፈንታ፡ከላይ፥
ሁሉንም፡የሚችል፡አምላክ፡ርስት፡ከአር
ያም፡ምንድር፡ነው?
፫፡ መዓትስ፡ለኃጢአተኛ፥
መለየትስ፡ለሚበድሉ፡አይደለችምን?
፬፡ መንገዴን፡አያይምን?
እርምጃዬንስ፡ሁሉ፡አይቈጥርምን?

፭፡፮፡ በእውነተኛ፡ሚዛን፡ልመዘን፥
እግዚአብሔርም፡ቅንነቴን፡ይወቅ።
በሐሰት፡ሄጄ፡እንደ፡ሆነ፡
እግሬም፡ለሽንገላ፡ቸኵላ፡እንደ፡ሆነ፥
፯፡ እርምጃዬ፡ከመንገድ፡ፈቀቅ፡ብሎ፥
ልቤም፡ዓይኔን፡ተከትሎ፥
ነውርም፡ከእጄ፡ጋር፡ተጣብቆ፡እንደ፡ሆነ፥
፰፡ እኔ፡ልዝራ፥ሌላ፡ሰውም፡ይብላው፤
የሚበቅለውም፡ሁሉ፡ይነቀል።

፱፡ ልቤ፡ወደ፡ሌላይቱ፡ሴት፡ጐምጅቶ፡እንደ፡
ሆነ፥
በባልንጀራዬም፡ደጅ፡አድብቼ፡እንደ፡ሆነ፥
፲፡ ሚስቴ፡ለሌላ፡ሰው፡ትፍጭ፥
ሌሎችም፡በእርስዋ፡ላይ፡ይጐንበሱ።
፲፩፡ ይህ፡ክፉ፡አበሳ፥
ፈራጆችም፡የሚቀጡበት፡በደል፡ነውና፤
፲፪፡ ይህ፡እስከ፡ጥፋት፡ድረስ፡የሚበላ፡እሳት፥
ቡቃያዬንም፡ሁሉ፡የሚነቅል፡ነውና።
፲፫፡ ወንድ፡ባሪያዬ፡ወይም፡ሴት፡ባሪያዬ፡ከእኔ፡
ጋር፡በተምዋገቱ፡ጊዜ፥
ሙግታቸውን፡ንቄ፡እንደ፡ሆነ፥

፲፬፤ እግዚአብሔር ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ ምን ፡ አደር ጋለሁ ?
በጐበኘኝ ፡ ጊዜ ፡ ምን ፡ እመልስለታለሁ ?
፲፭፤ እኔን ፡ በማኅፀን ፡ የፈጠረ ፡ እርሱንስ ፡ የፈጠ ረው ፡ አይደለምን ?
በማኅፀንስ ፡ ውስጥ ፡ የሠራን ፡ አንድ ፡ አይደለ ንምን ?

፲፮፤ ድሀውን ፡ ከልመናው ፡ ከልክዬ ፥
የመበለቲቱን ፡ ዓይን ፡ አጨልሜ ፡ እንደ ፡ ሆን ፥
፲፯፤ እንጀራዬን ፡ ለብቻዬ ፡ በልቼ ፡ እንደ ፡ ሆን ፥
ድሀ ፡ አደጉም ፡ ደግሞ ፡ ከእርሱ ፡ ሳይበላ ፡ ቀርቶ ፡ እንደ ፡ ሆን ፤
፲፰፤ እርሱን ፡ ግን ፡ ከታናሽነቴ ፡ ጀምሬ ፡ እንደ ፡ አባቱ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ አሳድጌው ፡ ነበር ፥
እርስዋንም ፡ ከእናቴ ፡ ማኅፀን ፡ ጀምሬ ፡ መራ ኋት ፤
፲፱፤ ራቁቱን ፡ የሆነው ፡ ሰው ፡ ሲጠፋ ፥
ወይም ፡ ድሀ ፡ ያለ ፡ ልብስ ፡ ሲሆን ፡ አይቼ ፡ እንደ ፡ ሆን ፥
፳፤ ጐንና ፡ ጐኑ ፡ ያልባረከችኝ ፥
በበጎቼም ፡ ጠጕር ፡ ያልሞቀ ፡ እንደ ፡ ሆን ፤
፳፩፤ በበሩ ፡ ረዳት ፡ ስላየሁ ፥
በድሀ ፡ አደጉ ፡ ላይ ፡ እጄን ፡ አንሥቼ ፡ እንደ ፡ ሆን ፥
፳፪፤ ትከሻዬ ፡ ከመሠረትዋ ፡ ትውደቅ ፥
ክንዴም ፡ ከመገናኛዋ ፡ ትሰበር ።
፳፫፤ የእግዚአብሔር ፡ መዓት ፡ አስደንግጦኛልና ፤
በክብሩም ፡ ፊት ፡ ምንም ፡ ለማድረግ ፡ አልቻ ልሁም ።

፳፬፤ ወርቅን ፡ ተስፋ ፡ አድርጌ ፥
ጥሩውንም ፡ ወርቅ ፡— በአንተ ፡ እታመናለሁ ፡ ብዬ ፡ እንደ ፡ ሆን ፤
፳፭፤ ሀብቴ ፡ ስለ ፡ በዛ ፥
እጄም ፡ ብዙ ፡ ስላገኘች ፡ ደስ ፡ ብሎኝ ፡ እንደ ፡ ሆን ፤
፳፮፤ ፀሐይ ፡ ሲበራ ፡
ጨረቃም ፡ በክብር ፡ ስትሄድ ፡ አይቼ ፥
፳፯፤ ልቤ ፡ በስውር ፡ ተታልሎ ፥
አፌም ፡ እጄን ፡ ስሞ ፡ እንደ ፡ ሆን ፤
፳፰፤ ልዑል ፡ እግዚአብሔርን ፡ በካድሁ ፡ ነበርና ፡
ይህ ፡ ደግሞ ፡ ፈራጆች ፡ የሚቀጡበት ፡ በደል ፡ በሆን ፡ ነበር ።

፳፱፤ በሚጠላኝ ፡ መጥፋት ፡ ደስ ፡ ብሎኝ ፡
ክፉ ፡ ነገርም ፡ ባገኘው ፡ ጊዜ ፡ ሐሤት ፡ አድርጌ ፡ እንደ ፡ ሆን ፤
፴፤ ነገር ፡ ግን ፡ በመርገም ፡ ነፍሱን ፡ በመሻት ፡
አንደበቴን ፡ ኃጢአት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ አልሰ ጠሁም ፤
፴፩፤ በድንኳኔ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡—
በከብቱ ፡ ሥጋ ፡ ያልጠገበ ፡ ማን ፡ ይገኛል ? ብለው ፡ እንደ ፡ ሆን ፤

፴፪፤ መጻተኛው ፡ ግን ፡ በሜዳ ፡ አያድርም ፡ ነበር ፥
ደጄንም ፡ ለመንገደኛ ፡ እከፍት ፡ ነበር ፤
፴፫፤ በደሌንም ፡ በብብቴ ፡ በመሸሸግ ፡
ኃጢአቴን ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ሰውሬ ፡ እንደ ፡ ሆን ፤
፴፬፤ ከሕዝብ ፡ ብዛት ፡ ፈርቼ ፥
የዘመዶቼም ፡ ንቀት ፡ አስደንግጦኝ ፥
ዝም ፡ ብዬ ፡ ከደጅ ፡ ያልወጣሁ ፡ እንደ ፡ ሆን ፤
፴፭፤ የሚያዳምጠኝ ፡ ምነው ፡ በኖረልኝ !
እነሆ ፡ የእጄ ፡ ምልክት ፤
ሁሉን ፡ የሚችል ፡ አምላክ ፡ ይመልስልኝ ፤
ከባላጋራዬ ፡ የተጻፈው ፡ የክስ ፡ ጽሑፍ ፡ ምነው ፡ በተገኘልኝ !
፴፮፤ በትከሻዬ ፡ ላይ ፡ እሸከመው ፥
አክሊልም ፡ አድርጌ ፡ በራሴ ፡ አስረው ፡ ነበር ፤
፴፯፤ የእርምጃዬን ፡ ቍጥር ፡ አስታውቀው ፥
እንደ ፡ አለቃም ፡ ሆኜ ፡ አቀርብለት ፡ ነበር ።
፴፰፤ እርሻዬ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ጮኾ ፡ እንደ ፡ ሆን ፥
ትልሞችዋም ፡ በአንድ ፡ ላይ ፡ አልቅሰው ፡ እንደ ፡ ሆን ፤
፴፱፤ ፍሬዋን ፡ ያለ ፡ ዋጋ ፡ በልቼ ፥
የባለቤቶችንም ፡ ነፍስ ፡ አሳዝኜ ፡ እንደ ፡ ሆን ፥
፵፤ በስንዴ ፡ ፋንታ ፡ አሜከላ ፥
በገብስም ፡ ፋንታ ፡ ኵርንችት ፡ ይውጣብኝ ።
የኢዮብ ፡ ቃል ፡ ተፈጸመ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

፩፤ ኢዮብም ፡ ራሱን ፡ ጻድቅ ፡ አድርጎ ፡ ነበርና ፡ እነዚያ ፡ ሦስቱ ፡ ሰዎች ፡ መመለስን ፡ ተዉ ። ፪፤ ከራም ፡ ወገን ፡ የሆነ ፡ የቡዛዊው ፡ የባርክኤል ፡ ልጅ ፡ የኤሊሁ ፡ ቍጣ ፡ ነደደ ፤ ከእግዚአብ ሔር ፡ ይልቅ ፡ ራሱን ፡ ጻድቅ ፡ አድርጎ ፡ ነበርና ፡ ኢዮብን ፡ ተቈጣው ። ፫፤ ደግሞም ፡ በኢዮብ ፡ ፈረ ዱበት ፡ እንጂ ፡ የሚገባ ፡ መልስ ፡ ስላላገኙ ፡ በሦ ስቱ ፡ ባልንጀሮቹ ፡ ላይ ፡ ተቈጣ ። ፬፤ ኤሊሁ ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ ይልቅ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ነበሩና ፡ ከኢ ዮብ ፡ ጋር ፡ መናገርን ፡ ጠብቆ ፡ ነበር ። ፭፤ ኤሊ ሁም ፡ በነዚህ ፡ በሦስቱ ፡ ሰዎች ፡ አፍ ፡ መልስ ፡ እንደሌለ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ቍጣው ፡ ነደደ ።

፮፤ የቡዛዊውም ፡ የባርክኤል ፡ ልጅ ፡ ኤሊሁ ፡ ተናገረ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—
እኔ ፡ በዕድሜ ፡ ታናሽ ፡ ነኝ ፥ እናንተ ፡ ግን ፡ ሽማግሌዎች ፡ ናችሁ ፤
ስለዚህም ፡ ሰጋሁ ፤ እውቀቴን ፡ እገልጥላችሁ ፡ ዘንድ ፡ ፈራሁ ።
፯፤ እንደዚህም ፡ አልሁ ፡— ዓመታት ፡ በተናገሩ ፡ ነበር ፥
የዓመታትም ፡ ብዛት ፡ ጥበብን ፡ በአስተማረች ፡ ነበር ።
፰፤ ነገር ፡ ግን ፡ በሰው ፡ ውስጥ ፡ መንፈስ ፡ አለ ፥
ሁሉንም ፡ የሚችል ፡ የአምላክ ፡ እስትንፋስ ፡ ማስተዋልን ፡ ይሰጣል ።
፱፤ በዕድሜ ፡ ያረጁ ፡ ጠቢባን ፡ አይደሉም ፥
ሽማግሌዎችም ፡ ፍርድን ፡ አያስተውሉም ።
፲፤ ስለዚህም ፡— ስሙኝ ፤

እኔ ፡ ደግሞ ፡ እውቀቴን ፡ እገልጥላችኋለሁ ፡
አልሁ ።

፲፩ እነሆ ፥ ቃላችሁን ፡ በትዕግሥት ፡ ጠበቅሁ ፤
የምትናገሩትን ፡ ነገር ፡ እስክትመረምሩ ፡ ድረስ ፡
ብልሃታችሁን ፡ አዳመጥሁ ።
፲፪ እንዲሁም ፡ ልብ ፡ አደረግሁ ፤
እነሆም ፥ በእናንተ ፡ መካከል ፡ ኢዮብን ፡ ያስረዳ ፥
ወይም ፡ ለቃሉ ፡ የመለሰ ፡ የለም ።
፲፫ እናንተም ፡— ጥበብን ፡ አግኝተናል ፤
እግዚአብሔር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡ አያሸንፈውም ፡ እንዳትሉ ፡ ተጠንቀቁ ።
፲፬ እርሱ ፡ ግን ፡ ቃሉን ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ አልተናገረም ፤
እኔም ፡ በንግግራችሁ ፡ አልመልስለትም ።

፲፭ እነርሱ ፡ ደነገጡ ፥ ዳግመኛም ፡ አልመለሱም ፤
የሚናገሩትንም ፡ አጡ ።
፲፮ እነርሱ ፡ አልተናገሩምና ፥
ቆመው ፡ ዳግመኛ ፡ አልመለሱምና ፡ እኔ ፡ በትዕግሥት ፡ እጠብቃለሁን ?
፲፯ እኔ ፡ ደግሞ ፡ ፈንታዬን ፡ እመልሳለሁ ፥
እውቀቴንም ፡ እገልጣለሁ ፤
፲፰ እኔ ፡ ቃል ፡ ተሞልቻለሁና ፥
በውስጤም ፡ ያለ ፡ መንፈስ ፡ አስገድዶኛልና ።
፲፱ በተሐ ፡ ጠጅ ፡ እንደ ፡ ተሞላና ፡ ሊቀደድ ፡ እንደ ፡ ቀረበ ፡ አቁማዳ ፥
ሊፈነዳ ፡ እንደማይችል ፡ እንደ ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡ አቁማዳ ፥ እነሆ ፥ አንጀቴ ፡ ሆነ ።
፳ ጥቂት ፡ እንድተነፍስ ፡ እናገራለሁ ፤
ከንፈሬን ፡ ገልጬ ፡ እመልሳለሁ ።
፳፩ ለሰው ፡ ፊት ፡ ግን ፡ አላደላም ፤
ሰውንም ፡ አላቈላምጥም ።
፳፪ በማቈላመጥ ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ አላውቅምና ፤
ያለዚያስ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ፈጥኖ ፡ ከሕይወቴ ፡ ይለየኝ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፫ ።

፩ ነገር ፡ ግን ፥ ኢዮብ ፡ ሆይ ፥ ንግግሬን ፡ እንድ ትሰማ ፥
ቃሌንም ፡ ሁሉ ፡ እንድታደምጥ ፡ እለምንሃለሁ ።
፪ እነሆ ፥ አፌን ፡ ከፍቻለሁ ፥
አንደበቴም ፡ በትናጋዬ ፡ ተናግሮአል ።
፫ ቃሌ ፡ የልቤን ፡ ቅንነት ፡ ያወጣል ፤
ከንፈሮቼም ፡ የሚያውቁትን ፡ በቅንነት ፡ ይናገራሉ ።
፬ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ፈጠረኝ ፥
ሁሉንም ፡ የሚችል ፡ የአምላክ ፡ እስትንፋስ ፡ ሕይወትን ፡ ሰጠኝ ።
፭ ይቻልህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ መልስልኝ ፤
ቃልህንም ፡ አዘጋጅተህ ፡ በፊቴ ፡ ቁም ።
፮ እነሆ ፥ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እኔ ፡ እንደ ፡ አንተ ፡ ነኝ ፤
እኔ ፡ ደግሞ ፡ ከጭቃ ፡ የተፈጠርሁ ፡ ነኝ ።
፯ እነሆ ፥ ግርማዬ ፡ አታስፈራህም ፥
እጄም ፡ አትከብድብህም ።

፰ በጆሮዬ ፡ ተናግረሃል ፥
የቃልህንም ፡ ድምፅ ፡ ሰምቻለሁ ፥ እንዲህም ፡ ብለሃል ፡—
፱ እኔ ፡ ያለ ፡ መተላለፍ ፡ ንጹሕ ፡ ነኝ ፤
ያለ ፡ ነውር ፡ ነኝ ፥ ኃጢአትም ፡ የለብኝም ፤
፲ እነሆ ፥ ምክንያት ፡ አግኝቶብኛል ፥
እንደ ፡ ጠላቱም ፡ ቈጥሮኛል ፤
፲፩ እግሬን ፡ በግንድ ፡ አጣበቀ ፥
መንገዴንም ፡ ሁሉ ፡ ተመለከተ ።

፲፪ እነሆ ፥ አንተ ፡ በዚህ ፡ ጻድቅ ፡ አይደለህም ፤
እግዚአብሔር ፡ ከሰው ፡ ይበልጣል ፡ ብዬ ፡ እመልስልሃለሁ ።
፲፫ አንተ ፡— ለቃሌ ፡ ሁሉ ፡ አይመልስልኝም ፡ ብለህ ፥
ስለ ፡ ምን ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ትከራከራለህ ?
፲፬ እግዚአብሔር ፡ በአንድ ፡ መንገድ ፡ በሌላም ፡ ይናገራል ፤
ሰው ፡ ግን ፡ አያስተውለውም ።
፲፭ በሕልም ፥ በሌሊት ፡ ራእይ ፥
አፍላ ፡ እንቅልፍ ፡ በሰዎች ፡ ላይ ፡ ሲወድቅ ፥
በአልጋ ፡ ላይ ፡ ተኝተው ፡ ሳሉ ፥
፲፮ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የሰዎችን ፡ ጆሮ ፡ ይከፍታል ፥
በተግሣጹም ፡ ያስደነግጣቸዋል ፥
፲፯ ሰውን ፡ ከክፉ ፡ ሥራው ፡ ይመልሰው ፡ ዘንድ ፥
ከሰውም ፡ ትዕቢትን ፡ ይሰውር ፡ ዘንድ ፤
፲፰ ነፍሱን ፡ ከጕድጓድ ፥
በሰይፍም ፡ እንዳይጠፋ ፡ ሕይወቱን ፡ ይጠብቃል ።

፲፱ ደግሞ ፡ በአልጋ ፡ ላይ ፡ በደዌ ፡ ይገሥጸዋል ፥
አጥንቱንም ፡ ሁሉ ፡ ያደነዝዛል ።
፳ ሕይወቱም ፡ እንጀራን ፥
ነፍሱም ፡ ጣፋጭ ፡ መብልን ፡ ትጠላለች ።
፳፩ ሥጋው ፡ እስከማይታይ ፡ ድረስ ፡ ይሰለስላል ፤
ተሸፍኖ ፡ የነበረውም ፡ አጥንት ፡ ይገለጣል ።
፳፪ ነፍሱ ፡ ወደ ፡ ጕድጓዱ ፥
ሕይወቱም ፡ ወደሚገድሉአት ፡ ቀርባለች ።

፳፫ የቀናውን ፡ መንገድ ፡ ለሰው ፡ ያስታውቀው ፡ ዘንድ ፥
ከሺህ ፡ አንድ ፡ ሆኖ ፡ የሚተረጕም ፡ መልአክ ፡ ቢገኝለት ፥
፳፬ እየራራለት ፡—
ቤዛ ፡ አግኝቻለሁና
ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ እንዳይወርድ ፡ አድነው ፡ ቢለው ፥
፳፭ ሥጋው ፡ እንደ ፡ ሕፃን ፡ ሥጋ ፡ ይለመልማል ፤
ወደ ፡ ጕብዝናውም ፡ ዘመን ፡ ይመለሳል ።
፳፮ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይጸልያል ፥
እርሱም ፡ ሞገስን ፡ ይሰጠዋል ፤

ፊቱንም፡ በደስታ፡ ያሳየዋል ፤
ለሰውም፡ ጽድቁን፡ ይመልስለታል ።
፳፯ እርሱም፡ በሰው፡ ፊት፡ እየዘመረ ፡—
እኔ፡ በድያለሁ፥ ቅኑንም፡ አጣምሜአለሁ ፤
የሚገባኝንም፡ ብድራት፡ አልተበቀልሁም ፤
፳፰ ነፍሴ፡ ወደ፡ ጕድጓድ፡ እንዳትወርድ፡ አድኖ
አታል፥
ሕይወቴም፡ ብርሃንን፡ ታያለች፡ ይላል ።

፳፱ እግዚአብሔር፡ ይህን፡ ሁሉ፡
ሁለት፡ ጊዜና፡ ሦስት፡ ጊዜ፡ ከሰው፡ ጋር፡
ያደርጋል ፤
፴ ይህም፡ ነፍሱን፡ ከጕድጓድ፡ ይመልስ፡ ዘንድ፥
በሕያዋንም፡ ብርሃን፡ ያበራ፡ ዘንድ፡ ነው ።
፴፩ ኢዮብ፡ ሆይ፥ አድምጥ፥ እኔንም፡ ስማ ፤
ዝም፡ በል፥ እኔም፡ እናገራለሁ ።
፴፪ ነገር፡ ቢኖርህ፡ መልስልኝ ፤
ትጸድቅ፡ ዘንድ፡ እወድዳለሁና፡ ተናገር ።
፴፫ ያለዚያም፡ እኔን፡ ስማ ፤
ዝም፡ በል፥ እኔም፡ ጥበብን፡ አስተምርሃለሁ ።

## ምዕራፍ፡ ፴፬ ።

፩ ኤሊሁም፡ ደግሞ፡ መለሰ፥ እንዲህም፡ አለ፡—
፪ እናንተ፡ ጥበበኞች፥ ቃሌን፡ ስሙ ፤
እናንተም፡ አዋቂዎች፥ ወደ፡ እኔ፡ አድምጡ ።
፫ ትናጋ፡ መብልን፡ እንደሚቀምስ፥
ጆሮ፡ ቃልን፡ ትለያለችና ።
፬ ቅን፡ የሆነውን፡ ነገር፡ እንምረጥ ፤
መልካሙንም፡ ነገር፡ በመካከላችን፡ እንወቅ ።
፭ ኢዮብ፡— እኔ፡ ጻድቅ፡ ነኝ፥
እግዚአብሔር፡ ማን፡ ፍርዴን፡ አስወገደ ፤
፮ ምንም፡ እውነተኛ፡ ብሆን፡ እንደ፡ ውሸተኛ፡
ተቈጠርሁ ፤
ምንም፡ ባልበድል፡ ቍስሌ፡ የማይፈወስ፡ ነው፡
ብሎአል ።
፯፰፱ ኢዮብም፡— በእግዚአብሔር፡ መደሰት፡
ለሰው፡ ምንም፡ አይጠቅምም፡ ብሎአልና፡
ከበደለኞች፡ ጋር፡ የሚተባበር፥
ከክፉ፡ ከሚያደርጉም፡ ጋር፡ የሚሄድ፥
መሳለቅን፡ እንደ፡ ውኃ፡ የሚጠጣ፡
እንደ፡ ኢዮብ፡ ያለ፡ ሰው፡ ማን፡ ነው ?

፲ ስለዚህ፡ እናንተ፡ አእምሮ፡ ያላችሁ፡ ሰዎች፥
ስሙኝ ፤
ክፋትን፡ ያደርግ፡ ዘንድ፡ ከእግዚአብሔር፥
በደልንም፡ ይሠራ፡ ዘንድ፡ ሁሉን፡ ከሚችል፡
አምላክ፡ ይራቅ ።
፲፩ ለሰው፡ ሥራውን፡ ይመልስለታል፥
ሰውም፡ እንደ፡ መንገዱ፡ ያገኝ፡ ዘንድ፡ ያደር
ጋል ።
፲፪ በእውነት፡ እግዚአብሔር፡ ክፉ፡ አይሠራም፥
ሁሉንም፡ የሚችል፡ አምላክ፡ ፍርድን፡ ጠማማ፡
አያደርግም ።
፲፫ ምድርን፡ አደራ፡ የሰጠው፡ ማን፡ ነው ?
ዓለምንስ፡ ሁሉ፡ በእርሱ፡ ላይ፡ ያኖረ፡ ማን፡
ነው ?
፲፬ እርሱ፡ ልቡን፡ ወደ፡ ራሱ፡ ቢመልስ፥
መንፈሱንና፡ እስትንፋሱን፡ ወደ፡ ራሱ፡ ቢሰ
በስብ፥
፲፭ ሥጋ፡ ለበሽ፡ ሁሉ፡ በአንድነት፡ ይጠፋል፥
ሰውም፡ ወደ፡ አፈር፡ ይመለሳል ።

፲፮ አስተዋይ፡ ብትሆን፡ ይህን፡ ስማ ፤
የንግግሬንም፡ ቃል፡ አድመጥ ።
፲፯ በውኑ፡ ጽድቅን፡ የሚጠላ፡ ይሠለጥናልን ?
ጻድቅና፡ ኃያል፡ የሆነውስ፡ በደለኛ፡ ታደርገ
ዋለህን ?
፲፰ ማንም፡ ሰው፡ ንጉሡን፡— በደለኛ፡ ነህ፥
መኳንንቱንም፡— ክፉዎች፡ ናችሁ፡ ይላልን ?
፲፱ እነርሱ፡ ሁሉ፡ የእጁ፡ ሥራ፡ ናቸውና፡
በአለቆች፡ ፊት፡ አያደላም፥
ባለጠጋውንም፡ ሰው፡ ከድሀው፡ ይበልጥ፡ አይ
መለከትም ።
፳ እነርሱ፡ በመንፈቀ፡ ሌሊት፡ በድንገት፡ ይሞ
ታሉ ፤
ሕዝቡ፡ ተንቀጥቅጦ፡ ያልፋል፥
ኃያላንም፡ ያለ፡ እጅ፡ ይነጠቃሉ ።

፳፩ ዓይኖቹ፡ በሰው፡ መንገድ፡ ላይ፡ ናቸው፥
እርምጃውንም፡ ሁሉ፡ ያያል ።
፳፪ ኃጢአትን፡ የሚሠሩ፡ ይሰወሩበት፡ ዘንድ፡
ጨለማ፡ ወይም፡ የሞት፡ ጥላ፡ የለም ።
፳፫ ሰው፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ለመፋረድ፡
እንዲመጣ፡
ጊዜ፡ አይወስንለትም ።
፳፬ ታላላቆችን፡ ያለ፡ ምርመራ፡ ይሰባብራል፥
በእነርሱም፡ ፋንታ፡ ሌሎችን፡ ያቆማል ።
፳፭ ሥራቸውን፡ ያውቃል ፤
እንዲደቀቁም፡ በሌሊት፡ ይገለብጣቸዋል ።
፳፮ ሰዎች፡ እያዩ፡ እንደ፡ ክፉዎች፡ ይመታቸዋል ፤
፳፯፳፰ የድሀውን፡ ልቅሶ፡ ወደ፡ እርሱ፡ ያደርሱ፡
ዘንድ፥
እርሱም፡ የችግረኛውን፡ ድምፅ፡ ይሰማ፡ ዘንድ፥
እርሱን፡ ከመከተል፡ ፈቀቅ፡ ብለዋልና፥
ከመንገዱም፡ ሁሉ፡ አንዱን፡ አልተመለከቱ
ምና ።
፳፱ በሕዝብ፡ ወይም፡ በሰው፡ ዘንድ፡ ቢሆን፥
እርሱ፡ ቢያሳርፍ፡ የሚፈርድ፡ ማን፡ ነው ?
ፊቱንስ፡ ቢሰውር፡ የሚያየው፡ ማን፡ ነው ?
፴ ይህም፡ ዝንጉ፡ ሰው፡ እንዳይነግሥ፥
ሕዝቡንም፡ የሚያጠምድ፡ እንዳይኖር፡ ነው ።

፴፩ እግዚአብሔርን፡— እኔ፡ ሳልበድል፡ ቅጣት፡
ተቀበልሁ ፤
፴፪ የማላየውን፡ ነገር፡ አንተ፡ አስተምረኝ ፤
ኃጢአትንም፡ ሠርቼ፡ እንደ፡ ሆነ፥
ደግሜ፡ አልሠራም፡ የሚለው፡ ማን፡ ነው ?
፴፫ በውኑ፡ አንተ፡ ጥለኸዋልና፡

ፍዳው፡አንተ፡እንደምትወድደው፡ይሆናልን?
አንተ፡ትመርጣለህ፡እንጂ፡እኔ፡አይደለሁም፤
ስለዚህ፡የምታውቀውን፡ተናገር።

፴፬፤ የሚሰሙኝ፡ጥበበኞች፡ሁሉ÷
አስተዋዮችም፡እንዲህ፡ይሉኛል፡—

፴፭፤ ኢዮብ፡ያለ፡እውቀት፡ተናግሮአል÷
ቃሉም፡በአእምሮ፡አይደለችም።

፴፮፤ ኢዮብ፡እስከ፡ፍጻሜ፡ድረስ፡ምነው፡በተ
ፈተነ፡ኖሮ!
እርሱ፡እንደ፡ክፉዎች፡መልሶአልና፤

፴፯፤ በኃጢአቱም፡ላይ፡ዓመፅን፡ጨምሮአልና÷
በእኛም፡መካከል፡በእጁ፡ያጨበጭባልና÷
ቃልንም፡በእግዚአብሔር፡ላይ፡ያበዛልና።

## ምዕራፍ ፡ ፴፭ ።

፩፤ ኤሊሁም፡ደግሞ፡መለሰ፡እንዲህም፡አለ፡—

፪፤ ይህ፡ጽድቅ፡እንደ፡ሆነ፡ታስባለህን?
ወይስ፡— በእግዚአብሔር፡ፊት፡እኔ፡ጻድቅ፡
ነኝ፡ትላለህን?

፫፤ አንተ፡— ምን፡ጥቅም፡አለህ?
ኃጢአት፡ሠርቼ፡ከማገኘው፡ይልቅ፡ኃጢ
አት፡ባልሠራ፡ኖሮ፡ምን፡እጠቀማለሁ?
ብለህ፡ጠይቀሃልና።

፬፤ እኔ፡ለአንተና፡ከአንተ፡ጋር፡ላሉ፡ለባልንጀ
ሮችህ፡እመልሳለሁ።

፭፤ ዓይኖችህን፡ወደ፡ሰማይ፡አቅንተህ፡እይ፤
ከአንተም፡ከፍ፡ከፍ፡ያሉትን፡ደመናት፡ተመ
ልከት።

፮፤ ኃጢአት፡ብትሠራ፡ምን፡ትጐዳዋለህ?
መተላለፍህስ፡ቢበዛ፡ምን፡ታደርገዋለህ?

፯፤ ጻድቅስ፡ብትሆን፡ምን፡ትሰጠዋለህ?
ወይስ፡ከእጅህ፡ምንን፡ይቀበላል?

፰፤ እንደ፡አንተ፡ያለውን፡ሰው፡ክፋትህ፡ይጐ
ዳዋል፤
ለሰውም፡ልጅ፡ጽድቅህ፡ይጠቅመዋል።

፱፤ ከግፍ፡ብዛት፡የተነሣ፡ሰዎች፡ይጮኻሉ፤
ከኃያላንም፡ክንድ፡የተነሣ፡ለእርዳታ፡ይጠ
ራሉ።

፲፡፲፩፤ ነገር፡ግን፡— በሌሊት፡መዝሙርን፡የሚሰጥ÷
ከምድርም፡እንስሶች፡ይልቅ፡የሚያስተምረን፡
ከሰማይም ፡ወፎች፡ይልቅ፡ጥበበኞች፡የሚ
ያደርገን፡
ፈጣሪዬ፡እግዚአብሔር፡ወዴት፡ነው?የሚል፡
የለም።

፲፪፤ በዚያ፡ስለ፡ክፉ፡ሰዎች፡ትዕቢት፡ይጮኻሉ÷
እርሱ፡ግን፡አይመልስላቸውም።

፲፫፤ በእውነት፡እግዚአብሔር፡ከንቱ፡ነገርን፡አይ
ሰማም÷
ሁሉን፡የሚችል፡አምላክም፡አይመለከተ
ውም፤

፲፬፤ ይልቁንም፡— አላየውም፤
ነገሩ፡በእርሱ፡ፊት፡ነው÷እኔም፡እጠብቀዋ
ለሁ፡ስትል።

፲፭፤ አሁን፡ግን፡በቍጣው፡አልጐበኘምና፡—
በኃጢአት፡እጅግ፡አያስብም፡ትላለህ።

፲፮፤ ስለዚህ፡ኢዮብ፡አፉን፡በከንቱ፡ይከፍታል÷
ያለ፡እውቀትም፡ቃሉን፡ያበዛል።

## ምዕራፍ ፡ ፴፮ ።

፩፤ ኤሊሁም፡ደግሞ፡መለሰ፡እንዲህም፡አለ፡—

፪፤ ገና፡ስለ፡እግዚአብሔር፡የሚነገር፡አለኝና፡
ጥቂት፡ቆየኝ÷እኔም፡አስታውቅሃለሁ።

፫፤ እውቀቴን፡ከሩቅ፡አመጣለሁ÷
ፈጣሪዬንም፡— ጻድቅ፡ነው፡እላለሁ።

፬፤ ቃሌ፡በእውነት፡ያለ፡ሐሰት፡ነው፤
በእውቀትም፡ፍጹም፡የሆነ፡ከአንተ፡ጋር፡
አለ።

፭፤ እነሆ÷እግዚአብሔር፡ኃያል፡ነው÷ማንንም፡
አይንቅም፤
እርሱም፡በማስተዋል፡ብርታት፡ኃያል፡ነው።

፮፤ እርሱ፡የበደለኞችን፡ሕይወት፡አያድንም፤
ለችግረኞች፡ግን፡ፍርዱን፡ይሰጣል።

፯፤ ዓይኑን፡ከጻድቃን፡ላይ፡አያርቅም፤
ለዘላለምም፡ከነገሥታት፡ጋር፡በዙፋን፡ላይ፡
ያስቀምጣቸዋል÷
እነርሱም፡ከፍ፡ከፍ፡ይላሉ።

፰፤ በሰንሰለት፡ቢታሰሩ÷
ወይም፡በችግር፡ገመድ፡ቢጠመዱ÷

፱፤ ሥራቸውንና፡መተላለፋቸውን፡
በትዕቢትም፡እንዳደረጉ፡ይናገራቸዋል።

፲፤ ጆሮአቸውን፡ለተግሣጽ፡ይከፍተዋል÷
ከኃጢአትም፡ይመለሱ፡ዘንድ፡ያዝዛቸዋል።

፲፩፤ ቢሰሙ፡ቢያገለግሉትም÷
ዕድሜአቸውን፡በልማት÷
ዘመናቸውንም፡በተድላ፡ይፈጽማሉ።

፲፪፤ ባይሰሙ፡ግን፡በሰይፍ፡ይጠፋሉ÷
ያለ፡እውቀትም፡ይሞታሉ።

፲፫፤ ዝንጉዎች፡ግን፡ቍጣን፡ያዘጋጃሉ፤
እርሱም፡ባሰራቸው፡ጊዜ፡አይጮኹም።

፲፬፤ በሕፃንነታቸው፡ሳሉ፡ይሞታሉ÷
ሕይወታቸውም፡በሰዶማውያን፡መካከል፡
ይጠፋል።

፲፭፤ የተቸገረውን፡በችግሩ፡ያድነዋል፤
በመከራም፡ጆሮአቸውን፡ይገልጣል።

፲፮፤ እንዲሁም፡አንተን፡ከመከራ፡
ችግር፡ወደሌለበት፡ወደ፡ሰፊ፡ስፍራ፡በወ
ሰደህ፡ነበር÷
በማዕድህ፡ላይ፡የተዘጋጀውም፡ስብ፡በሞላ
በት፡ነበር።

፲፯፤ አንተ፡ግን፡በበደለኞች፡ፍርድ፡የተሞላህ፡
ነህ፤
ስለዚህ፡ፍርድና፡ብይን፡ይይዙሃል።

፲፰፤ ቍጣ፡ለስድብ፡አያታልልህ፤
የማማለጃም፡ብዛት፡ፈቀቅ፡አያድርግህ።

፲፱፤ ባለጠግነትህ፡የኃይልህም፡ብርታት፡ሁሉ፡
ያለ፡ችግር፡እንድትሆን፡ሊረዳህ፡ይችላልን?

፳፡ ወገኖች፡ከስፍራቸው፡የሚወጡበትን፡ሌሊት፡
አትመኝ ።
፳፩፡ ከመከራ፡ይልቅ፡ይህን፡መርጠሃልና፡
ኃጢአትን፡እንዳትመለከት፡ተጠንቀቅ ።

፳፪፡ እነሆ ፥ እግዚአብሔር፡በኃይሉ፡ከፍ፡ያለውን፡
ነገር፡ያደርጋል ፤
እንደ፡እርሱስ፡ያለ፡አስተማሪ፡ማን፡ነው ?
፳፫፡ መንገዱን፡ማን፡አዘዘለት ?
ወይስ፡— ኃጢአትን፡ሠርተሃል፡የሚለው፡
ማን፡ነው ?
፳፬፡ ሰዎች፡የዘመሩትን፡ሥራውን፡ታከብር፡ዘንድ፡
አስብ ።
፳፭፡ ሰዎች፡ሁሉ፡ተመልክተውታል ፤
ሰውም፡ከሩቅ፡ያየዋል ።
፳፮፡ እነሆ ፥ እግዚአብሔር፡ታላቅ፡ነው ፥ እኛም፡
አናውቀውም ፤
የዘመኑም፡ቍጥር፡አይመረመርም ።
፳፯፡ የውኃውን፡ነጠብጣብ፡ወደ፡ላይ፡ይስባል ፥
ዝናብም፡ከጉም፡ይንጠባጠባል ፤
፳፰፡ ደመናት፡ያዘንባሉ ፥
በሰዎችም፡ላይ፡በብዙ፡ያንጠባጥባሉ ።
፳፱፡ የደመናውንም፡መዘርጋት ፥
የማደሪያውንም፡ነጐድጓድ፡የሚያስተውል፡
ማን፡ነው ?
፴፡ እነሆ ፥ በዙሪያው፡ብርሃኑን፡ይዘረጋል ፤
የባሕሩንም፡ጥልቀት፡ይከድናል ።
፴፩፡ በእነዚህ፡በአሕዛብ፡ላይ፡ይፈርዳል ፤
ብዙም፡ምግብ፡ይሰጣል ።
፴፪፡ እጆቹን፡በብርሃን፡ይሰውራል ፥
በጠላቱም፡ላይ፡ይወጣ፡ዘንድ፡ያዝዘዋል ።
፴፫፡ የነጐድጓድ፡ድምፅ፡ስለ፡እርሱ፡ይናገራል ፤
እንስሶችም፡ደግሞ፡ስለሚመጣው፡ውሽን
ፍር፡ይጮኻሉ ።

ምዕራፍ፡፴፯ ።

፩፡ ስለዚህም፡ልቤ፡ተንቀጠቀጠ ፥
ከስፍራውም፡ተንቀሳቀሰ ።
፪፡ የድምፁን፡መትመም፡ስሙ ፥
ከአፉም፡የሚወጣውን፡ጕርምርምታ፡አድ
ምጡ ።
፫፡ እርሱን፡ወደ፡ሰማያት፡ሁሉ፡ታች ፥
ብርሃኑንም፡ወደ፡ምድር፡ዳርቻ፡ይሰድዳል ።
፬፡ በስተ፡ኋላው፡ድምፅ፡ይጮኻል ፤
በግርማውም፡ድምፅ፡ያንጐደጕዳል ፤
ድምፁም፡በተሰማ፡ጊዜ፡
መብረቁን፡አይከለክልም ።
፭፡ እግዚአብሔር፡በድምፁ፡ድንቅኛ፡ያንጐደ
ጕዳል ፤
እኛም፡የማናስተውለውን፡ታላቅ፡ነገር፡ያደ
ርጋል ።
፮፡ በረዶውንና፡ውሽንፍሩን፡ብርቱንም፡ዝናብ፡—
በምድር፡ላይ፡ውደቁ፡ይላል ።
፯፡ ሰው፡ሁሉ፡ሥራውን፡ያውቅ፡ዘንድ፡
የሰውን፡ሁሉ፡እጅ፡ያትማል ።
፰፡ አውሬዎቹም፡ወደ፡ጫካው፡ይገባሉ ፥
በዋሻቻቸውም፡ይቀመጣሉ ።
፱፡ ከተሰወረ፡ማደሪያውም፡ዐውሎ፡ነፋስ ፥
ከሰሜንም፡ብርድ፡ይወጣል ።
፲፡ ከእግዚአብሔር፡እስትንፋስ፡ውርጭ፡ተሰጥ
ቶአል ፤
የውኆችም፡ስፋት፡ይጠብባል ።
፲፩፡ የውኃውንም፡ሙላት፡በደመና፡ላይ፡ይጭናል ፤
የብርሃኑንም፡ደመና፡ይበታትናል ፤
፲፪፡፲፫፡ ለተግሣጽ፡ወይም፡ለምድሩ፡ወይም፡ለም
ሕረት፡ቢሆን ፥
ሰው፡በሚኖርበት፡ዓለም፡ላይ፡
ያዘዘውን፡ሁሉ፡ያደርግ፡ዘንድ፡
ፈቃዱ፡ወደ፡መራቸው፡ይዞራል ።

፲፬፡ ኢዮብ፡ሆይ ፥ ይህን፡ስማ ፤
ቁም ፥ የእግዚአብሔርንም፡ተአምራት፡አስብ ።
፲፭፡ በውኑ፡እግዚአብሔር፡እንዴት፡እንደሚያ
ዝዛቸው ፥
የደመናውንም፡ብርሃን፡እንዴት፡እንደሚያ
በራ፡አውቀሃልን ?
፲፮፡ ወይስ፡የደመናውን፡ሚዛን ፥
ወይስ፡በእውቀት፡ፍጹም፡የሆነውን፡ተአ
ምራት፡አውቀሃልን ?
፲፯፡ በደቡብ፡ነፋስ፡ምድር፡ጸጥ፡ባለች፡ጊዜ ፥
ልብስህ፡የሞቀች፡አንተ፡ሆይ ፥
፲፰፡ እንደ፡ቀለጠ፡መስተዋት፡
ብርቱ፡የሆኑትን፡ሰማያት፡ከእርሱ፡ጋር፡
ልትዘረጋ፡ትችላለህን ?
፲፱፡ እኛ፡ከጨለማ፡የተነሣ፡በሥርዓት፡መናገር፡
አንችልምና፡
የምንለውን፡አስታውቀን ።
፳፡ ማንም፡በእርሱ፡ላይ፡ቢናገር፡ፈጽሞ፡ይዋ
ጣልና፡
እኔ፡እናገር፡ዘንድ፡ብወድድ፡ሰው፡ይነግረ
ዋልን ?

፳፩፡ አሁንም፡ነፋስ፡አልፎ፡ከጠራቸው፡በኋላ ፥
ሰው፡በሰማያት፡የሚበራውን፡ብርሃን፡ሊመ
ለከት፡አይችልም ።
፳፪፡ ከሰሜን፡ወርቅ፡የሚመስል፡ጌጠኛ፡ብር
ሃን፡ይወጣል ፤
በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡የሚያስፈራ፡ግርማ፡
አለ ።
፳፫፡ ሁሉን፡የሚችል፡አምላክን፡እናገኝ፡ዘንድ፡
አንችልም ፤
በኃይል፡ታላቅ፡ነው ፤
በፍርድና፡በጽድቅም፡አያስጨንቅም ።
፳፬፡ ስለዚህ፡ሰዎች፡ይፈሩታል ፤
በልባቸውም፡ጠቢባን፡የሆኑትን፡ሁሉ፡
አይመለከትም ።

ምዕራፍ ፡ ፴፰ ።

፩፡ እግዚአብሔርም ፡ በሀውሎ ፡ ነፋስ ፡ ውስጥ ፡
ሆኖ ፡ ለኢዮብ ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—
፪፡ ያለ ፡ እውቀት ፡ በሚነገር ፡ ቃል ፡
ምክርን ፡ የሚያጨልም ፡ ይህ ፡ ማነው ?
፫፡ እንግዲህ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ወገብህን ፡ ታጠቅ ፤
እጠይቅሃለሁ ÷ አንተም ፡ ተናገረኝ ።

፬፡ ምድርን ፡ በመሠረትሁ ፡ ጊዜ ፡ አንተ ፡ ወዴት ፡
ነበርህ ?
ታስተውል ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ ተናገር ።
፭፡ ብታውቅስ ፡ መሠፈሪያዋን ፡ የወሰነ ÷
በላይዋስ ፡ የመለኪያ ፡ ገመድ ፡ የዘረጋ ፡ ማን ፡
ነው ?
፮፡፯፡ አጥቢያ ፡ ከከቦች ፡ በአንድነት ፡ ሲዘምሩ ÷
የእግዚአብሔርም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ እልል ፡ ሲሉ ÷
መሠረቶችዋ ፡ በምን ፡ ላይ ፡ ተተክለው ፡ ነበር ?
የማዕዘንዋንስ ፡ ድንጋይ ፡ ያቆመ ፡ ማን ፡ ነው ?

፰፡ ከማኅፀን ፡ እንደሚወጣ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ÷
ባሕርን ፡ በመዝጊያዎች ፡ የዘጋ ፡ ማን ፡ ነው ?
፱፡ ደመናውን ፡ ለልብሱ ÷
ጨለማንም ፡ ለመጠቅለያው ፡ አደረግሁ ፤
፲፡ ድንበሩን ፡ በዙሪያው ፡ አድርጌ ÷
መወርወሪያዎቹንና ፡ መዝጊያዎቹን ፡ አኑሬ ፡—
፲፩፡ እስከዚህ ፡ ድረስ ፡ ድረሺ ÷ አትለፊ ፤
በዚህም ፡ ለትዕቢተኛው ፡ ማዕበልሽ ፡ ገደብ ፡
ይሁን ፡ አልሁ ።

፲፪፡፲፫፡ የምድርን ፡ ዳርቻ ፡ ይይዝ ፡ ዘንድ ÷
ከእርስዋም ፡ በደለኞች ፡ ይናወጡ ፡ ዘንድ ÷
በውኑ ፡ ከተወለድህ ፡ ጀምሮ ፡ ማለዳን ፡ አዝዘ
ሃልን ?
ለወገግታም ፡ስፍራውን ፡ አስታውቀኸዋልን ?
፲፬፡ ጭቃ ፡ ከማኅተም ፡ በታች ፡ እንደሚለወጥ ፡ እን
ዲሁ ፡ እርስዋ ፡ ትለወጣለች ፤
ነገርም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ተቀልሞአል ።
፲፭፡ ከበደለኞች ፡ ብርሃናቸው ፡ ተከልክሎአል ÷
ከፍ ፡ ያለውም ፡ ክንድ ፡ ተሰብሮአል ።

፲፮፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ምንጭስ ፡ ውስጥ ፡ ገብተሃልን ?
በቀላዩስ ፡ መሠረት ፡ ውስጥ ፡ ተመላልሰሃልን ?
፲፯፡ የሞት ፡ በሮች ፡ ተገልጠውልሃልን ?
የሞትንስ ፡ ጥላ ፡ ደጆች ፡ አይተሃልን ?
፲፰፡ ምድርንስ ፡ በስፋትዋ ፡ አስተውለሃታልን ?
ሁሉን ፡ አውቀህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ተናገር ።

፲፱፡፳፡ ወደ ፡ ዳርቻው ፡ ትነዳው ፡ ዘንድ ÷
ወደ ፡ ቤቱም ፡ የሚያደርሰውን ፡ ጐዳና ፡ ታውቅ ፡
ዘንድ ÷
የብርሃን ፡ መኖሪያ ፡ መንገድ የት ፡ ነው ?
የጨለማውስ ፡ ቦታ ፡ ወዴት ፡ አለ ?
፳፩፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ተወልደህ ፡ ነበርና ÷
የዕድሜህም ፡ ቍጥር ፡ ብዙ ፡ ነውና ፡
በእውነት ፡ አንተ ፡ ሳታውቅ ፡ አትቀርም ።
፳፪፡ በውኑ ፡ ወደ ፡ በረዶው ፡ ቤተ ፡ መዛግብት ፡ ገብ
ተሃልን ?
የበረዶውንስ ፡ ቅንጣት ፡ ቤተ ፡ መዛግብት ፡ አይ
ተሃልን ?
፳፫፡ ይኸውም ፡ ለመከራ ፡ ጊዜ ፡ ለሰልፍና ፡ ለጦር
ነት ፡ ቀን ፡ የጠበቅሁት ፡ ነው ።
፳፬፡ ብርሃንስ ፡ በምን ፡ መንገድ ፡ ይከፈላል ?
የምሥራቅስ ፡ ነፋስ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እንዴት ፡
ይበተናል ?

፳፭፡፳፮፡ በድማውንና ፡ ውድማውን ፡ እንዲያጠግብ ÷
ሣሩንም ፡ እንዲያበቅል ÷
፳፯፡ ማንም ፡ በሌለበት ፡ ምድር ፡ ላይ ÷
ሰውም ፡ በሌለበት ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ላይ ፡ ዝናብን ፡
ያዘንብ ፡ ዘንድ ÷
ለፈሳሹ ፡ ውኃ ፡ መንዶልዶያውን ÷
ወይስ ፡ ለሚያንጐደጕድ ፡ መብረቅ ፡ መንገድን ፡
ያበጀ ፡ ማን ፡ ነው ?
፳፰፡ በውኑ ፡ ለዝናብ ፡ አባት ፡ አለውን ?
ወይስ ፡ የጠልን ፡ ነጠብጣብ ፡ የወለደ ፡ ማን ፡ ነው ?
፳፱፡ በረዶስ ፡ ከማን ፡ ማኅፀን ፡ ወጣ ?
የሰማዩንስ ፡ አመዳይ ፡ ማን ፡ ወለደው ?
፴፡ ውኆች ፡ እንደ ፡ ድንጋይ ፡ ጠነከሩ ÷
የቀላዩም ፡ ፊት ፡ ረግቶአል ።

፴፩፡ በውኑ ፡ የሰባቱን ፡ ከዋክብት ፡ ዘለላ ፡ ታስር ፡
ዘንድ ÷
ወይስ ፡ ኦሪዮን ፡ የሚባለውን ፡ ኮከብ ፡ ትፈታ ፡
ዘንድ ፡ ትችላለህን ?
፴፪፡ ወይስ ፡ ማዛሮት ፡ የሚባሉትን ፡ ከዋክብት ፡ በጊ
ዜያቸው ፡ ታወጣ ፡ ዘንድ ÷
ወይስ ፡ ድብ ፡ የሚባለውን ፡ ኮከብ ፡ ከልጆቹ ፡
ጋር ፡ ትመራ ፡ ዘንድ ፡ ትችላለህን ?
፴፫፡ የሰማይን ፡ ሥርዓት ፡ ታውቃለህን ?
በምድርስ ፡ ላይ ፡ እንዲሠለጥን ፡ ልታደርግ ፡
ትችላለህን ?
፴፬፡ የውኆች ፡ ብዛት ፡ ይሸፍንህ ፡ ዘንድ ፡
ቃልህን ፡ ወደ ፡ ደመናት ፡ ታነሣ ፡ ዘንድ ፡ ትች
ላለህን ?
፴፭፡ መብረቆች ፡ ሄደው ፡— እነሆ ÷ እዚህ ፡ አለን ፡
ይሉህ ፡ ዘንድ ፡
ልትልካቸው ፡ ትችላለህን ?
፴፮፡ በውስጡስ ፡ ጥበብን ፡ ያኖረ ÷
ለሰውስ ፡ ልብ ፡ ማስተዋልን ፡ የሰጠ ፡ ማን ፡ ነው ?
፴፯፡፴፰፡ የሰማይን ፡ ደመና ፡ በጥበቡ ፡ ሊቈጥር ፡ የሚ
ችል ፡ ማን ፡ ነው ?
ትቢያ ፡ በተበጠበጠ ፡ ጊዜ ÷
ጓሎቹም ፡ በተጣበቁ ፡ ጊዜ ÷
የሰማይን ፡ ረዋት ፡ ሊያዘነብል ፡ የሚችል ፡ ማን ፡
ነው ?

፴፱፡፵፡ በዋሾቻቸው ፡ ውስጥ ፡ ተጋድመው ÷

በጫካም ፡ ውስጥ ፡ አድብተው ፡ ሳሉ ፥
ለአንበሳይቱ ፡ አደን ፡ ታድናለህን ?
የልጆችዋንስ ፡ ነፍስ ፡ ታጠግብ ፡ ዘንድ ፡ ትች
ላለህን ?
፵፩ ፡ ልጆቹ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሲጮኹ ፥
የሚበሉትም ፡ አጥተው ፡ ሲቅበዘበዙ ፥
ለቍራ ፡ መብልን ፡ የሚሰጠው ፡ ማን ፡ ነው ?

## ምዕራፍ ፡ ፴፱ ።

፩ ፡ የበረሃ ፡ ፍየል ፡ የምትወልድበትን ፡ ጊዜ ፡
ታውቃለህን ?
ዋላይቱስ ፡ የምታምጥበትን ፡ ጊዜ ፡ ትመለከ
ታለህን ?
፪ ፡ እርስዋ ፡ የምትፈጽመውንስ ፡ ወራት ፡ ትቈጥራ
ለህን ?
የምትወልድበትንስ ፡ ጊዜ ፡ ታውቃለህን ?
፫ ፡ ይንበረከካሉ ፥ ልጆቻቸውንም ፡ ይወልዳሉ ፥
ከምጣቸውም ፡ ያርፋሉ ።
፬ ፡ ልጆቻቸው ፡ ይጠነክራሉ ፥
በሜዳም ፡ ያድጋሉ ፤
ይወጣሉ ፥ ወደ ፡ እነርሱም ፡ አይመለሱም ።

፭ ፡ የሜዳውስ ፡ አህያ ፡ አርነት ፡ ማን ፡ አወጣው ?
የበረሃውንስ ፡ አህያ ፡ ከእስራቱ ፡ ማን ፡ ፈታው ?
፮ ፡ በረሃውን ፡ ለእርሱ ፡ ቤት ፡ አድርጌ ፡ ሰጠሁት ፤
መኖሪያውም ፡ በጨው ፡ ምድር ፡ ነው ።
፯ ፡ በከተማ ፡ ውካታ ፡ ይዘብታል ፤
የነጂውን ፡ ጩኸት ፡ አይሰማም ።
፰ ፡ ተራራውን ፡ እንደ ፡ መሰምርያው ፡ ይመለከተ
ዋል ፥
ለምለሙንም ፡ ሁሉ ፡ ይፈልጋል ።

፱ ፡ ጐሽ ፡ ያገለግልህ ፡ ዘንድ ፡ ይታዘዛልን ?
ወይስ ፡ በግርግምህ ፡ አጠገብ ፡ ያድራልን ?
፲ ፡ ጐሽ ፡ ይተልምልህ ፡ ዘንድ ፡ ትጠምደዋለህን ?
ወይስ ፡ ከአንተ ፡ በኋላ ፡ በእርሻ ፡ ላይ ፡ ይጐለ
ጕላልን ?
፲፩ ፡ ጕልበቱስ ፡ ብርቱ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ትታመነዋለህን ?
ተግባርህንስ ፡ ለእርሱ ፡ ትተዋለህን ?
፲፪ ፡ ዘርህንስ ፡ ይመልስልህ ፡ ዘንድ ፥
በአውድማህስ ፡ ያከማችልህ ፡ ዘንድ ፡ ትታመነ
ዋለህን ?
፲፫ ፡ የሰጐን ፡ ክንፍ ፡ በደስታ ፡ ይንቀሳቀሳል ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ክንፉና ፡ ላባው ፡ ጭምተኛ ፡ ነውን ?
፲፬ ፡ እንቍላልዋን ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ ትተዋለች ፥
በአፈርም ፡ ውስጥ ፡ ታሞቀዋለች ፤
፲፭ ፡ እግር ፡ ይሰብረው ፡ ዘንድ ፥
የምድረ ፡ በዳም ፡ አውሬ ፡ ይረግጠው ፡ ዘንድ ፡
ትረሳለች ።
፲፮ ፡ የእርስዋ ፡ እንዳልሆኑ ፡ በልጆችዋ ፡ ትጨከ
ናለች ፤
በከንቱም ፡ ብትሠራ ፡ አትፈራም ፤
፲፯ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጥበብን ፡ ከእርስዋ ፡ ከልክሎ
አልናና ፥
ማስተዋልንም ፡ አልሰጣትምና ።
ወደ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ስትል ፡ ፲፰ ፡
በፈረስና ፡ በፈረሰኛው ፡ ትሳለቃለች ።

፲፱ ፡ ለፈረስ ፡ ጕልበቱን ፡ ሰጥተኸዋልን ?
አንገቱንስ ፡ ጋማ ፡ አልብሰኸዋልን ?
፳ ፡ እንደ ፡ አንበጣስ ፡ አፈናጠርኸውን ?
የማንኰራፋቱ ፡ ክብር ፡ የሚያስፈራ ፡ ነው ።
፳፩ ፡ በኮቴው ፡ በሸለቆው ፡ ውስጥ ፡ ይጐደፍራል ፥
በጉልበቱም ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤
ሰይፍም ፡ የታጠቁትን ፡ ለመገናኘት ፡ ይወጣል ።
፳፪ ፡ በፍርሃት ፡ ላይ ፡ ይስቃል ፥
እርሱም ፡ አይደነግጥም ፤
ከሰይፍም ፡ ፊት ፡ አይመለስም ።
፳፫ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ የፍላጻ ፡ ከረጢና ፡ ብልጭልጭ ፡
የሚል ፡ ጦር ፡
ሰላጢንም ፡ ያንኳኳሉ ።
፳፬ ፡ በጭከኔና ፡ በቍጣ ፡ መሬትን ፡ ይውጣል ፤
የመለከትም ፡ ድምፅ ፡ ቢሰማ ፡ አይቆምም ።
፳፭ ፡ የመለከትም ፡ ድምፅ ፡ ሲሰማ ፡—እሰይ! ይላል ፤
ከሩቅ ፡ ሆኖ ፡ ሰልፍንና ፡ የአለቆቹን ፡ ጩኸት ፥
የሠራዊቱንም ፡ ውካታ ፡ ያሸታል ።

፳፮ ፡ በውኑ ፡ ከጥበብህ ፡ የተነሣ ፡ ጭልፊት ፡ ያንዣ
ብባልን ?
ወይስ ፡ ክንፎቹን ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ ይዘረጋልን ?
፳፯ ፡ በአፍህ ፡ ትእዛዝ ፡ ንስር ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላልን?
ቤቱንስ ፡ በአርያም ፡ ላይ ፡ ያደርጋልን ?
፳፰ ፡ በገደል ፡ ላይ ፡ ይኖራል ፤
በገደሉ ፡ ገመገምና ፡ በጥጉ ፡ ያድራል ።
፳፱ ፡ በዚያም ፡ ሆኖ ፡ የሚነጥቀውን ፡ ይጐበኛል ፤
ዓይኑም ፡ በሩቅ ፡ ትመለከታለች ።
፴ ፡ ጫጩቶቹም ፡ ደም ፡ ይጠጣሉ ፤
በድን ፡ ባለበትም ፡ ስፍራ ፡ እርሱ ፡ በዚያ ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵ ።

፩ ፡ እግዚአብሔርም ፡ መለሰ ፡ ኢዮብንም ፡ እን
ዲህ ፡ አለው ፡—
፪ ፡ በውኑ ፡ የሚከራከር ፡ ሰው ፡ ሁሉን ፡ ከሚችል ፡
አምላክ ፡ ጋር ፡ ይከራከራልን ?
ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ የሚዋቀስ ፡ እርሱ ፡ ይመ
ልስለት ።

፫ ፡ ኢዮብም ፡ መለሰ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ እን
ዲህ ፡ አለው ፡—
፬ ፡ እነሆ ፥ እኔ ፡ ወራዳ ፡ ሰው ፡ ነኝ ፤ የምመልስልህ ፡
ምንድር ፡ ነው ?
እጄን ፡ በአፌ ፡ ላይ ፡ እጭናለሁ ።
፭ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ተናገርሁ ፥ አልመልስምም ፤
ሁለተኛ ፡ ጊዜም ፥ ከእንግዲህ ፡ ወዲህም ፡ አል
ናገርም ።

፮ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ውስጥ ፡
ሆኖ ፡ ለኢዮብ ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—

፯ እንግዲህ ፡ እንደ ፡ ወንድ ፡ ወገብህን ፡ ታጠቅ ፤
እጠይቅሃለሁ ÷ አንተም ፡ ተናገረኝ ።
፰ በውኑ ፡ ፍርዴን ፡ ታፈርሳለህን ?
አንተስ ፡ ጻድቅ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ በእኔ ፡ ትፈር
ዳለህን ?
፱ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ክንድ ፡ ያለ ፡ ክንድ ፡
አለህን ?
ወይስ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ባለ ፡ ድምፅ ፡ ታንጐደ
ጕዳለህን ?

፲ በታላቅነትና ፡ በልዕልና ፡ ተላበስ ፤
በክብርና ፡ በግርማም ፡ ተጐናጸፍ ።
፲፩ የቍጣህን ፡ ፈሳሽ ፡ አፍስስ ፤
ትዕቢተኛውንም ፡ ሁሉ ፡ ተመልከተህ ፡ አዋ
ርደው ።
፲፪ ትዕቢተኛውንም ፡ ሁሉ ፡ ተመልከት ÷ ዝቅ ፡
ዝቅም ፡ አድርገው ፤
በደለኞችንም ፡ ወዲያውኑ ፡ እርገጣቸው ።
፲፫ በአፈር ፡ ውስጥ ፡ በአንድነት ፡ ሰውራቸው ፤
በተሸሸገም ፡ ስፍራ ፡ ፊታቸውን ፡ ሸፍን ።
፲፬ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቀኝ ፡ እጅህ ፡ታድንህ ፡ ዘንድ ፡
እንድትችል ፡
እኔ ፡ ደግሞ ፡ እመሰክርልሃለሁ ።

፲፭ ከአንተ ፡ ጋር ፡ የሠራሁትን ፡ ጉማሬ ÷ እስኪ ÷
ተመልከት ፤
እንደ ፡ በሬ ፡ ሣር ፡ ይበላል ።
፲፮ እነሆ ÷ ብርታቱ ፡ በወገቡ ፡ ውስጥ ፡ ነው ፤
ኃይሉም ፡ በሆዱ ፡ ጅማት ፡ ውስጥ ፡ ነው ።
፲፯ ጅራቱን ፡ እንደ ፡ ጥድ ፡ ዛፍ ፡ ያወዛውዛል ፤
የወርቹ ፡ ጅማት ፡ የተጐነጐነ ፡ ነው ።
፲፰ አጥንቱ ፡ እንደ ፡ ናስ ፡ አገዳ ፡ ነው ፤
አካላቱ ፡ እንደ ፡ ብረት ፡ ዘንጎች ፡ ናቸው ።
፲፱ እርሱ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍጥረት ፡ አውራ ፡ ነው ፤
ሠሪውም ፡ ሰይፉን ፡ ሰጠው ።
፳ የሜዳ ፡ እንስሶች ፡ ሁሉ ፡ የሚጫወቱበት ፡ ተራራ ፡
ምግብን ፡ ያበቅልለታል ።
፳፩ ጥላ ፡ ካለው ፡ ዛፍ ፡ በታች ÷
በደንገልና ፡ በረግረግ ፡ ውስጥ ፡ ይተኛል ።
፳፪ ጥላ ፡ ያለው ፡ ዛፍ ፡ በጥላው ፡ ይሰውረዋል ፤
የወንዝ ፡ አኻያ ፡ ዛፎች ፡ ይከብቡታል ።
፳፫ እነሆ ÷ ወንዙ ፡ ቢጐርፍ ፡ አይደነግጥም ፤
ዮርዳኖስም ፡ እስከ ፡ አፉ ፡ ድረስ ፡ ቢፈስስ ፡
እርሱ ፡ ይተማመናል ።
፳፬ ዓይኖቹ ፡ እያዩ ፡ ይያዛልን ?
አፍንጫውስ ፡ በወጥመድ ፡ ይበሳልን ?

፳፭ በውኑ ፡ አዞውን ፡ በመቃጥን ፡ ታወጣለህን ?
ምላሱንስ ፡ በገመድ ፡ ታስረዋለህን ?
፳፮ ወይስ ፡ ስናጋ ፡ በአፍንጫው ፡ ታደርጋለህን ?
ወይስ ፡ በችንካር ፡ ጕንጩን ፡ ትበሳለህን ?
፳፯ በውኑ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እጅግ ፡ ይለምናልን ?
በጣፈጠስ ፡ ቃል ፡ ይናገርሃልን ?
፳፰ በውኑ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ይገባልን ?
ወይስ ፡ ለዘላለም ፡ ባሪያ ፡ ታደርገዋለህን ?
፳፱ ከወፍ ፡ ጋር ፡ እንደምትጫወት ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
ትጫወታለህን ?
ወይስ ፡ ለሴት ፡ ባሪያዎችህ ፡ ታስረዋለህን ?
፴ አጥማጆች ፡ በእርሱ ፡ ይከራከራሉን ?
ወይስ ፡ ነጋዴዎች ፡ ያከፍሉታልን ?
፴፩ በውኑ ፡ ቁርበቱን ፡ በጭሬ ÷
ራሱንስ ፡ በዓሣ ፡ ጦር ፡ ትሞላዋለህን ?
፴፪ እጅህን ፡ በላዩ ፡ ጫን ፤
ሰልፉን ፡ አስብ ÷ እንግዲህም ፡ አትድገም ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፩ ።

፩ እነሆ ÷ ተስፋው ፡ ከንቱ ፡ ነው ፤
ያየው ፡ ሁሉ ፡ ስንኳ ፡ በፊቱ ፡ ይዋረዳል ።
፪ ያንቀሳቅሰውም ፡ ዘንድ ፡ የሚደፍር ፡ የለም ፤
እንግዲህ ፡ በፊቴ ፡ መቆም ፡ የሚችል ፡ ማን ፡ ነው ?
፫ እመልስለትስ ፡ ዘንድ ፡ መጀመሪያ ፡ የሰጠኝ ፡
ማን ፡ ነው ?
ከሰማይ ፡ ሁሉ ፡ በታች ፡ ያለው ፡ ገንዘቤ ፡ ነው ።

፬ ስለ ፡ አካላቱና ፡ ስለ ፡ ብርቱ ፡ ኃይሉ ÷
ስለ ፡ መልካም ፡ ሰውነቱ ፡ ዝም ፡ አልልም ።
፭ የውጪ ፡ ልብሱን ፡ ማን ፡ ይገፋል ?
በጥንድ ፡ መንጋጋውስ ፡ ውስጥ ፡ ማን ፡ ይገባል ?
፮ የፊቱንስ ፡ ደጆች ፡ የሚከፍት ፡ ማን ፡ ነው ?
በጥርሶቹ ፡ ዙሪያ ፡ ግርማ ፡ አለ ።
፯ ቅርፊቶቹ ፡ ጠንካራ ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ እርሱ ፡ ትዕቢ
ተኛ ፡ ነው ፤
በጠባብ ፡ ማተሚያ ፡ እንደ ፡ ታተሙ ፡ ናቸው ።
፰ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ የተቀራረቡ ፡ ናቸውና ፡
ነፋስ ፡ በመካከላቸው ፡ መግባት ፡ አይችልም ።
፱ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ የተገጣጠሙ ፡ ናቸው ፤
እስከማይለያዩም ፡ ድረስ ፡ ተያይዘዋል ።
፲ እንጥሽታው ፡ ብልጭታ ፡ ያወጣል ÷
ዓይኖቹም ፡ እንደ ፡ ወገግታ ፡ ናቸው ።
፲፩ ከአፉ ፡ ፋናዎች ፡ ይወጣሉ ÷
የእሳትም ፡ ፍንጣሪ ፡ ይረጫል ።
፲፪ እንደ ፡ ፈላ ፡ ድስትና ፡ እንደሚቃጠል ፡ ሸምበቆ ፡
ከአፍንጫው ፡ ጢስ ፡ ይወጣል ።
፲፫ እስትንፋሱ ፡ ከሰልን ፡ ታቃጥላለች ÷
ነበልባልም ፡ ከአፉ ፡ ይወጣል ።
፲፬ በአንገቱ ፡ ኃይል ፡ ታድራለች ፤
ግርማ ፡ በፊቱ ፡ ይዘፍናል ።
፲፭ የሥጋውም ፡ ቅርፊት ፡ የተጣበቀ ፡ ነው ፤
እስከማይንቀሳቀሱም ፡ ድረስ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡
ጸንተዋል ።
፲፮ ልቡ ፡ እንደ ፡ ድንጋይ ፡ የደነደነ ፡ ነው ፤
እንደ ፡ ወፍጮ ፡ ድንጋይ ፡ የጸና ፡ ነው ።
፲፯ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ ኃያላን ፡ ይፈራሉ ፤
ከድንጋጤም ፡ የተነሣ ፡ ይብዳሉ ።
፲፰ ሰይፍና ፡ ጦር ÷ ፍላጻና ፡ መውጊያም ፡ ቢያገ
ኙት ፡ አያሸንፉትም ።
፲፱ ብረትን ፡ እንደ ፡ ገለባ ÷
ናስንም ፡ እንደ ፡ ነቀዘ ፡ እንጨት ፡ ይቈጥራ

ቸዋል ።

፳፰ ፍላጻ ፡ ሊያበርረው ፡ አይችልም ፤
የወንጭፍም ፡ ድንጋዮች ፡ እንደ ፡ ገለባ ፡ ይሆኑለታል ።

፳፱ በሎታውን ፡ እንደ ፡ ገለባ ፡ ይቈጥረዋል ፤
ሰላጢኑም ፡ ሲሰበቅ ፡ ይስቃል ።

፴ ታቹ ፡ እንደ ፡ ስለታም ፡ ገል ፡ ነው ፤
እንደ ፡ መዳመጫም ፡ በጭቃ ፡ ላይ ፡ ያልፋል ።

፴፩ ቀላዩን ፡ እንደ ፡ ድስት ፡ ያፈላዋል ፤
ባሕሩንም ፡ እንደ ፡ ሽቱ ፡ ምንቸት ፡ ያደርገዋል ።

፴፪ በስተ ፡ ኋላው ፡ ብሩህ ፡ መንገድን ፡ ያበራል ፤
ቀላዩም ፡ ሽበት ፡ ይመስላል ።

፴፫ ያለ ፡ ፍርሃት ፡ የተፈጠረ ፥
እንደ ፡ እርሱ ፡ ያለ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የለም ።

፴፬ ከፍ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ይመለከታል ፤
በትዕቢተኞችም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፪ ።

፩ ኢዮብም ፡ መለሰ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ እንዲህ ፡ አለው ፦

፪ ሁሉን ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ ቻይ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፥
አሳብህም ፡ ይከለከል ፡ ዘንድ ፡ ከቶ ፡ እንደማይቻል ፡ አወቅሁ ።

፫ ያለ ፡ እውቀት ፡ ምክርን ፡ የሚሰውር ፡ ማን ፡ ነው?
ስለዚህ ፡ እኔ ፡ የማላስተውለውን ፥
የማላውቀውንም ፡ ድንቅ ፡ ነገር ፡ ተናግሬአለሁ ።

፬ አባክህ ፥ ስማኝ ፥ እኔም ፡ ልናገር ፤
እጠይቅህማለሁ ፥ አንተም ፡ ተናገረኝ ።

፭ መስማትንስ ፡ በጆሮ ፡ በመስማት ፡ ሰምቼ ፡ ነበር ፤
አሁን ፡ ግን ፡ ዓይኔ ፡ አየችህ ፤

፮ ስለዚህ ፡ ራሴን ፡ እንቃለሁ ፤
በአፈርና ፡ በአመድ ፡ ላይ ፡ ተቀምጬ ፡ እጸጸታለሁ ።

፯ እግዚአብሔርም ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ለኢዮብ ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቴማናዊውን ፡ ኤልፋዝን ፦ እንደ ፡ ባሪያዬ ፡ እንደ ፡ ኢዮብ ፡ ቅንን ፡ ነገር ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ አልተናገራችሁምና ፡ ቍጣዬ ፡ በአንተና ፡ በሁለቱ ፡ ባልንጀሮችህ ፡ ላይ ፡ ነድዶአል ። ፰ አሁን ፡ እንግዲህ ፡ ሰባት ፡ ወይፈኖችና ፡ ሰባት ፡ አውራ ፡ በጎች ፡ ይዛችሁ ፡ ወደ ፡ ባሪያዬ ፡ ወደ ፡ ኢዮብ ፡ ዘንድ ፡ ሂዱ ፥ የሚቃጠልንም ፡ መሥዋዕት ፡ ስለ ፡ ራሳችሁ ፡ አሳርጉ ፤ ባሪያዬም ፡ ኢዮብ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ይጸልያል ፥ እኔም ፡ እንደ ፡ ስንፍናችሁ ፡ እንዳላደርግባችሁ ፡ ፊቱን ፡ እቀበላለሁ ፤ እንደ ፡ ባሪያዬ ፡ እንደ ፡ ኢዮብ ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ አልተናገራችሁምና ። ፱ ቴማናዊውም ፡ ኤልፋዝ ፡ ሹሐዊውም ፡ በልዳዶስ ፡ ናዕማታዊውም ፡ ሶፋር ፡ ሄደው ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዛቸው ፡ አደረጉ ፤ እግዚአብሔርም ፡ የኢዮብን ፡ ፊት ፡ ተቀበለ ።

፲ ኢዮብም ፡ ስለ ፡ ወዳጆቹ ፡ በጸለየ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምርኮውን ፡ መለሰለት ፤ እግዚአብሔርም ፡ ቀድሞ ፡ በነበረው ፡ ፋንታ ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ አድርጎ ፡ ለኢዮብ ፡ ሰጠው ። ፲፩ ወንድሞቹና ፡ እኅቶቹ ፡ ቀድሞም ፡ ያውቁት ፡ የነበሩት ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጡ ፥ በቤቱም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ እንጀራ ፡ በሉ ፤ ስለ ፡ እርሱም ፡ አዘኑለት ፥ እግዚአብሔርም ፡ ካመጣበት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አጽናኑት ፤ እያንዳንዳቸውም ፡ ብርና ፡ የወርቅ ፡ ቀለበት ፡ ሰጡት ። ፲፪ እግዚአብሔርም ፡ ከፊተኛው ፡ ይልቅ ፡ የኋለኛውን ፡ ለኢዮብ ፡ ባረከ ፤ አሥራ ፡ አራት ፡ ሺህም ፡ በጎች ፥ ስድስት ፡ ሺህም ፡ ግመሎች ፥ አንድ ፡ ሺህም ፡ ጥማድ ፡ በሬዎች ፥ አንድ ፡ ሺህም ፡ እንስት ፡ አህዮች ፡ ነበሩት ። ፲፫ ደግሞም ፡ ሰባት ፡ ወንዶችና ፡ ሦስት ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ሆኑለት ። ፲፬ የመጀመሪያይቱንም ፡ ስም ፡ ይሚማ ፥ የሁለተኛይቱንም ፡ ስም ፡ ቃስያ ፥ የሦስተኛይቱንም ፡ ስም ፡ አማልቶያስ ፡ ቂራስ ፡ ብሎ ፡ ሰየማቸው ። ፲፭ እንደ ፡ ኢዮብ ፡ ሴቶች ፡ ልጆችም ፡ ያሉ ፡ የተዋቡ ፡ ሴቶች ፡ በአገሩ ፡ ሁሉ ፡ አልተገኙም ፤ አባታቸውም ፡ ከወንድሞቻቸው ፡ ጋር ፡ ርስት ፡ ሰጣቸው ። ፲፮ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ኢዮብ ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ኖረ ፥ ልጆቹንና ፡ የልጅ ፡ ልጆቹንም ፡ እስከ ፡ አራት ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ አየ ። ፲፯ ኢዮብም ፡ ሸምግሎ ፡ ዕድሜም ፡ ጠግቦ ፡ሞተ ።

# መ ዝ ሙ ረ ፡ ዳ ዊ ት ።

## መዝሙር ፡ ፩ ።

፩፤ ምስጉን ፡ ነው ፡ በክፉዎች ፡ ምክር ፡ ያልሄደ ፥
በኃጢአተኞችም ፡ መንገድ ፡ ያልቆመ ፥
በዋዘኞችም ፡ ወንበር ፡ ያልተቀመጠ ።
፪፤ ነገር፡ግን፡በእግዚአብሔር፡ሕግ፡ደስ፡ይለዋል፥
ሕጉንም ፡ በቀንና ፡ በሌሊት ፡ ያስባል ።
፫፤ እርሱም ፡ በውኃ ፡ ፈሳሾች ፡ ዳር ፡ እንደ ፡ ተተከለች ፥
ፍሬዋን ፡ በየጊዜዋ ፡ እንደምትሰጥ ፥
ቅጠልዋም ፡ እንደማይረግፍ ፡ ዛፍ ፡ ይሆናል ፤
የሚሠራውም ፡ ሁሉ ፡ ይከናወንለታል ።
፬፤ ክፉዎች ፡ እንዲህ ፡ አይደሉም ፥
ነገር ፡ ግን ፡ ነፋስ ፡ ጠርጎ ፡ እንደሚወስደው ፡ ትቢያ ፡ ናቸው ።
፭፤ ስለዚህ ፡ ክፉዎች ፡ በፍርድ ፥
ኃጢአተኞችም ፡ በጻድቃን ፡ ማኅበር ፡ አይቆሙም ።
፮፤ እግዚአብሔር ፡ የጻድቃንን ፡ መንገድ ፡ ያውቃልና ፥
የክፉዎች ፡ መንገድ ፡ ግን ፡ ትጠፋለች ።

## መዝሙር ፡ ፪ ።

፩፤ አሕዛብ ፡ ለምን ፡ ያጕረመርማሉ ?
ወገኖችስ ፡ ለምን ፡ ከንቱን ፡ ይናገራሉ ?
፪፤ የምድር ፡ ነገሥታት ፡ ተነሡ ፥
አለቆችም ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በመሲሑ ፡ ላይ ፡
እንዲህ ፡ ሲሉ ፡ ተማከሩ ፡—
፫፤ ማሰርያቸውን ፡ እንበጥስ ፥
ገመዳቸውንም ፡ ከእኛ ፡ እንጣል ።
፬፤ በሰማይ ፡ የሚኖር ፡ እርሱ ፡ ይሥቃል ፥
ጌታም ፡ ይሣለቅባቸዋል ።
፭፤ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በቍጣው ፡ ይናገራቸዋል ፥
በመዓቱም ፡ ያውካቸዋል ።
፮፤ እኔ ፡ ግን ፡ ንጉሤን ፡ ሾምሁ ፡
በተቀደሰው ፡ ተራራዬ ፡ በጽዮን ፡ ላይ ።
፯፤ ትእዛዙን ፡ እናገራለሁ ፤
እግዚአብሔር ፡ አለኝ ፡— አንተ ፡ ልጄ ፡ ነህ ፥
እኔ ፡ ዛሬ ፡ ወለድሁህ ።
፰፤ ለምነኝ ፥ አሕዛብን ፡ ለርስትህ ፡
የምድርንም ፡ ዳርቻ ፡ ለግዛትህ ፡ እሰጥሃለሁ ።
፱፤ በብረት ፡ በትር ፡ ትጠብቃቸዋለህ ፥
እንደ ፡ ሸክላ ፡ ሠሪ ፡ ዕቃም ፡ ትቀጠቅጣቸዋለህ ።
፲፤ አሁንም ፡ እናንተ ፡ ነገሥታት ፥ ልብ ፡ አድርጉ ፤
እናንተ ፡ የምድር ፡ ፈራጆችም ፥ ተገሠጹ ።
፲፩፤ ለእግዚአብሔር ፡ በፍርሃት ፡ ተገዙ ፥
በረዓድም ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ።
፲፪፤ ተግሣጹን ፡ ተቀበሉ ፡ ጌታ ፡ እንዳይቈጣ ፡
እናንተም ፡ በመንገድ ፡ እንዳትጠፉ ፥
ቍጣው ፡ ፈጥና ፡ ትነድዳለችና ።
በእርሱ ፡ የታመኑ ፡ ሁሉ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ።

## መዝሙር ፡ ፫ ።

ከልጁ ፡ ከአቤሴሎም ፡ ፊት ፡ በሸሸ ፡ ጊዜ ፡
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ፥ የሚያስጨንቁኝ ፡ ምንኛ ፡ በዙ !
በኔ ፡ ላይ ፡ የሚቆሙት ፡ ብዙ ፡ ናቸው ።
፪፤ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ነፍሴን ፡—
አምላክሽ ፡ አያድንሽም ፡ አሉዋት ።
፫፤ አንተ ፡ ግን ፥ አቤቱ ፥ መጠጊያዬ ፡ ነህ ፥
ክብሬንና ፡ ራሴንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ የምታደርገው ፡ አንተ ፡ ነህ ።
፬፤ በቃሌ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እጮኻለሁ ፥
ከተቀደሰ ፡ ተራራውም ፡ ይሰማኛል ።
፭፤ እኔ ፡ ተኛሁ ፡ አንቀላፋሁም ፤
እግዚአብሔርም ፡ ደግፎኛልና ፡ ነቃሁ ።
፮፤ ከሚከብቡኝ ፡ ከአእላፍ ፡ ሕዝብ ፡ አልፈራም ።
፯፤ ተነሥ ፥ አቤቱ ፤ አምላኬ ፡ ሆይ ፥ አድነኝ ፤
አንተ ፡ የጠላቶቼን ፡ መንጋጋ ፡ መትተሃልና ፥
የክፉዎችንም ፡ ጥርስ ፡ ሰብረሃልና ።
፰፤ ማዳን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነው ፥
በረከትህም ፡ በሕዝብህ ፡ ላይ ፡ ነው ።

## መዝሙር ፡ ፬ ።

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፡ በበገናዎች ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ የጽድቄ ፡ አምላክ ፡ በጠራሁት ፡ ጊዜ ፡ መለሰልኝ ፥
በጭንቀቴም ፡ አሰፋህልኝ ፤
ማረኝ ፥ ጸሎቴንም ፡ ስማ ።
፪፤ እናንተ ፡ የሰው ፡ ልጆች ፥ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ልባችሁን ፡ ታከብዳላችሁ ?
ከንቱ ፡ ነገርን ፡ ለምን ፡ ትወድዳላችሁ ? ሐሰትንም ፡ ለምን ፡ ትሻላችሁ ?
፫፤ እግዚአብሔር ፡ በጻድቁ ፡ እንደ ፡ ተገለጠ ፡ እወቁ ፤
እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ በተጣራሁ ፡ ጊዜ ፡ ይሰማኛል ።
፬፤ ተቈጡ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ኃጢአትን ፡ አታድርጉ ፤
በመኝታችሁ ፡ ሳላችሁ ፡ በልባችሁ ፡ አስቡ ፤ ዝም ፡ በሉ ።
፭፤ የጽድቅን ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዉ ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ታመኑ ።
፮፤ በጎውን ፡ ማን ፡ ያሳየናል ? የሚሉ ፡ ብዙ ፡ ናቸው ።
አቤቱ ፥ የፊትህ ፡ ብርሃን ፡ በላያችን ፡ ታወቀ ።
፯፤ በልቤ ፡ ደስታን ፡ ጨመርህ ፤
ከስንዴ ፡ ፍሬና ፡ ከወይን ፡ ከዘይትም ፡ ይልቅ ፡ በዛ ።
፰፤ በሰላም ፡ እተኛለሁ ፡ አንቀላፋለሁም ፤
አቤቱ ፥ አንተ ፡ ብቻህን ፡ በእምነት ፡ አሳድረኸኛልና ።

## መዝሙር ፡ ፭ ።

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፡ በዋሽንት ፤
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ÷ ቃሌን ፡ አድምጥ ÷
ጩኸቴንም ፡ አስተውል ፤
፪ የልመናዬን ፡ ቃል ፡ አድምጥ ÷
ንጉሤና ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ÷
አቤቱ ÷ ወደ ፡ አንተ ፡ እጸልያለሁና ።
፫ በማለዳ ፡ ድምፄን ፡ ትሰማለህ ÷
በማለዳ ፡ በፊትህ ፡ እቆማለሁ ÷ እጠብቃለሁም ።
፬ አንተ ፡ በደልን ፡ የማትወድድ ፡ አምላክ ፡ ነህና ፤
ክፉ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አያድርም ።
፭ በከንቱ ፡ የሚመኩ ፡ በዓይኖችህ ፡ ፊት ፡ አይኖሩም ፤
ክፉ ፡ አድራጊዎችን ፡ ሁሉ ፡ ጠላህ ።
፮ ሐሰትን ፡ የሚናገሩትን ፡ ታጠፋቸዋለህ ፤
ደም ፡ አፍሳሹንና ፡ ሸንጋዩን ፡ ሰው ፡ እግዚአብሔር ፡ ይጸየፋል ።
፯ እኔ ፡ ግን ፡ በምሕረትህ ፡ ብዛት ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ እገባለሁ ፤
አንተን ፡ በመፍራት ፡ ወደ ፡ ቅድስናህ ፡ መቅደስ ፡ እሰግዳለሁ ።
፰ አቤቱ ÷ ስለ ፡ ጠላቶቼ ፡ በጽድቅህ ፡ ምራኝ ፤
መንገዴን ፡ በፊትህ ፡ አቅና ።
፱ በአፋቸው ፡ እውነት ፡ የለምና ÷
ልባቸውም ፡ ከንቱ ፡ ነው ፤
ጉሮሮአቸው ፡ የተከፈተ ፡ መቃብር ፡ ነው ፤
በምላሳቸው ፡ ይሸነግላሉ ።
፲ አቤቱ ÷ ፍረድባቸው ÷ በምክራቸውም ፡ ይውደቁ ፤
ስለ ፡ ክፋታቸውም ፡ ብዛት ፡ አሳድዳቸው ÷
እነርሱ ፡ ዐምፀውብሃልና ።
፲፩ በአንተ ፡ የሚታመኑት ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፤
ለዘላለሙ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ÷ እነርሱንም ፡ ትጠብቃለህ ፤
ስምህንም ፡ የሚወድዱ ፡ ሁሉ ፡ በአንተ ፡ ይመካሉ ።
፲፪ አንተ ፡ ጻድቁን ፡ ትባርከዋለህና ፤
አቤቱ ÷ እንደ ፡ ጋሻ ፡ በሞገስ ፡ ከለልኸን ።

## መዝሙር ፡ ፮ ።

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፡ በበገናዎች ፡ ስለ ፡ ስምንተኛ ፡
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ÷ በቍጣህ ፡ አትቅሠፈኝ ÷
በመዓትህም ፡ አትገሥጸኝ ።
፪ ድውይ ፡ ነኝና ፡ አቤቱ ÷ ማረኝ ፤
አጥንቶቼ ፡ ታውከዋልና ፡ ፈውሰኝ ።
፫ ነፍሴም ፡ እጅግ ፡ ታወከች ፤
አንተም ፡ አቤቱ ÷ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ነው ?
፬ አቤቱ ÷ ተመለስ ፡ ነፍሴንም ፡ አድናት ÷
ስለ ፡ ቸርነትህም ፡ አድነኝ ።
፭ በሞት ፡ የሚያስብህ ፡ የለምና ÷
በሲኦልም ፡ የሚያመሰግንህ ፡ ማን ፡ ነው ?
፮ በጭንቀቴ ፡ ደክሜያለሁ ፤
ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ አልጋዬን ፡ አጥባለሁ ÷
በዕንባዬም ፡ መኝታዬን ፡ አርሳለሁ ።
፯ ዓይኔ ፡ ከቍጣ ፡ ዕንባ ፡ የተነሣ ፡ ታወከች ፤
ከጠላቶቼ ፡ ሁሉ ፡ የተነሣ ፡ አረጀሁ ።
፰ ዓመፃን ፡ የምታደርጉ ፡ ሁሉ ÷ ከእኔ ፡ ራቁ ÷
እግዚአብሔር ፡ የልቅሶዬን ፡ ቃል ፡ ሰምቶአልና ።
፱ እግዚአብሔር ፡ ልመናዬን ፡ ሰማኝ ፤
እግዚአብሔር ፡ ጸሎቴን ፡ ተቀበለ ።
፲ ጠላቶቼ ፡ ሁሉ ፡ ይፈሩ ፡ እጅግም ፡ ይጐስቍሉ ፤
ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ይመለሱ ÷ በፍጥነትም ፡ ይፈሩ ።

## መዝሙር ፡ ፯ ።

ስለ ፡ ብንያማዊ ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ ኩዝ ፡ ቃል ፡ ለእግዚአብሔር ፡
የዘመረው ፡ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ፡ አምላኬ ÷ በአንተ ፡ ታመንሁ ፤
ከሚያሳድዱኝ ፡ ሁሉ ፡ አድነኝና ፡ አውጣኝ ÷
፪ ነፍሴን ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ነጥቀው ፡ እንዳይሰብሩዋት ÷
የሚያድንና ፡ የሚታደግ ፡ ሳይኖር ።
፫ አቤቱ ፡ አምላኬ ÷ እንዲህስ ፡ ከደረግሁ ÷
ዓመፃም ፡ በእጄ ፡ ቢኖር ÷
፬ ክፉ ፡ ላደረጉብኝም ፡ ክፉን ፡ መልሼላቸው ፡ ብሆን ÷
ጠላቴንም ፡ በከንቱ ፡ ገፍቼው ፡ ብሆን ÷
፭ ጠላት ፡ ነፍሴን ፡ ያሳድዳት ፡ ያግኛትም ÷
ሕይወቴንም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ይርገጣት ÷
ክብሬንም ፡ በትቢያ ፡ ላይ ፡ ያዋርዳት ።
፮ አቤቱ ÷ በመዓትህ ፡ ተነሥ ÷
በጠላቶቼ ፡ ላይ ፡ በቍጣ ፡ ተነሣባቸው ፤
አቤቱ ፡ አምላኬ ÷ በዘዘኸው ፡ ትእዛዝ ፡ ንቃ ።
፯ የአሕዛብም ፡ ጉባኤ ፡ ይከብብሃል ÷
በእነርሱም ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ከፍታ ፡ ተመለስ ።
፰ እግዚአብሔር ፡ በአሕዛብ ፡ ይፈርዳል ፤
አቤቱ ÷ እንደ ፡ ጽድቄ ፡ ፍረድልኝ ÷
እንደ ፡ የዋህነቴም ፡ ይሁንልኝ ።
፱ የኃጥአን ፡ ክፋት ፡ ይጥፋ ÷
ጻድቁን ፡ ግን ፡ አቅና ፤
እግዚአብሔር ፡ ልቡናንና ፡ ኩላሊትን ፡ ይመረምራል ።
፲ እግዚአብሔር ፡ የጽድቅ ፡ ጋሻዬ ፡ ነው ፡
ልበ ፡ ቅኖችን ፡ የሚያድናቸው ።
፲፩ እግዚአብሔር ፡ የእውነት ፡ ዳኛ ፡ ነው ÷
ኃይለኛም ፡ ታጋሽም ፡ ነው ÷
ሁልጊዜም ፡ አይቈጣም ።
፲፪ በትመለሱ ፡ ግን ፡ ሰይፉን ፡ ይስላል ÷
ቀስቱን ፡ ገተረ ፡ አዘጋጀም ፤
፲፫ የሞት ፡ መሣርያንም ፡ አዘጋጀበት ÷
ፍላጻዎቹንም ፡ የሚቃጠሉ ፡ አደረገ ።
፲፬ እነሆ ÷ በዓመፃ ፡ ተጨነቀ ፡
ጉዳትን ፡ ፀነሰ ፡ ኃጢአትንም ፡ ወለደ ።
፲፭ ጕድጓድን ፡ ማሰ ፡ ቈፈረም ።
በደረገውም ፡ ጕድጓድ ፡ ይወድቃል ።

፲፮ ጉዳቱ ፡ በራሱ ፡ ይመለሳል ፥
ዓመፃውም ፡ በአናቱ ፡ ላይ ፡ ትወርዳለች ።
፲፯ እግዚአብሔርን ፡ እንደ ፡ ጽድቁ ፡ መጠን ፡ አመሰግናለሁ ፥
ለልዑል ፡ እግዚአብሔርም ፡ ስም ፡ እዘምራለሁ ።

### መዝሙር ፡ ፰ ።

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፡ በዋሽንት ፤
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ፡ ጌታችን ፥ ስምህ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ እጅግ ፡ ተመሰገነ ፥
ምስጋናህ ፡ በሰማዮች ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎአልና ።
፪ ከሕፃናትና ፡ ከሚጠቡ ፡ ልጆች ፡ አፍ ፡ ምስጋናን ፡ አዘጋጀህ ፡ ስለ ፡ ጠላትህ ፥
ጠላትንና ፡ ቂመኛን ፡ ለማጥፋት ።
፫ የጣቶችህን ፡ ሥራ ፡ ሰማዮችን ፡ በየሁ ፡ ጊዜ ፥
ጨረቃንና ፡ ከዋክብትን ፡ አንተ ፡ የሠራሃቸውን ፥
፬ ታስበው ፡ ዘንድ ፡ ሰው ፡ ምንድር ፡ ነው ?
ትጐበኘውም ፡ ዘንድ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
፭ ከመላእክት ፡ እጅግ ፡ ጥቂት ፡ አሳነስኸው ፤
በክብርና ፡ በምስጋና ፡ ዘውድ ፡ ከለልኸው ።
፮ በእጆችህም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሾምኸው ፤
ሁሉን ፡ ከእግሮቹ ፡ በታች ፡ አስገዛህለት ፥
፯ በጎችንም ፡ ላሞችንም ፡ ሁሉ ፥
ደግሞም ፡ የምድረ ፡ በዳውን ፡ እንስሶች ፥
፰ የሰማይንም ፡ ወፎች ፡ የባሕርንም ፡ ዓሦች ፥
በባሕር ፡ መንገድ ፡ የሚሄደውንም ፡ ሁሉ ።
፱ አቤቱ ፡ ጌታችን ፥ ስምህ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ እጅግ ፡ ተመሰገነ ።

### መዝሙር ፡ ፱ ።

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በሙትላቤን ፤
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ፥ በልቤ ፡ ሁሉ ፡ አመሰግንሃለሁ ፥
ተአምራትህንም ፡ ሁሉ ፡ እነግራለሁ ።
፪ በአንተ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፥ ሐሤትንም ፡ አደርጋለሁ ፤
ልዑል ፡ ሆይ ፥ ለስምህ ፡ እዘምራለሁ ።
፫ ጠላቶቼ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ በተመለሱ ፡ ጊዜ ፥
ይሰናከላሉ ፡ ከፊትህም ፡ ይጠፋሉ ።
፬ ፍርዴንና ፡ በቀሌን ፡ አድርገህልኛልና ፤
ጽድቅን ፡ እየፈረድህ ፡ በዙፋንህ ፡ ላይ ፡ ተቀመጥህ ።
፭ አሕዛብን ፡ ገሠጽህ ፥ ዝንጉዎችንም ፡ አጠፋህ ፥
ስማቸውንም ፡ ለዘላለም ፡ ደመሰስህ ።
፮ ጠላቶች ፡ በጦር ፡ ለዘላለም ፡ ጠፉ ፥
ከተሞቻቸውንም ፡ አፈረስህ ፥
ዝክራቸውም ፡ በአንድነት ፡ ጠፋ ።
፯ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ፥
ዙፋኑንም ፡ ለመፍረድ ፡ አዘጋጀ ፤
፰ እርሱም ፡ ዓለምን ፡ በጽድቅ ፡ ይፈርዳታል ፥
አሕዛብንም ፡ በቅንነት ፡ ይዳኛቸዋል ።
፱ እግዚአብሔርም ፡ ለድሆች ፡ መጠጊያ ፡ ሆናቸው ፥
እርሱም ፡ በመከራቸው ፡ ጊዜ ፡ ረዳታቸው ፡ ነው ።
፲ ስምህን ፡ የሚያውቁ ፡ ሁሉ ፡ በአንተ ፡ ይታመናሉ ፥
አቤቱ ፥ የሚሹህን ፡ አትተዋቸውምና ።
፲፩ በጽዮን ፡ ለሚኖር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዘምሩ ፥
በአሕዛብም ፡ መካከል ፡ አደራረጉን ፡ ንገሩ ፤
፲፪ ደማቸውን ፡ የሚመራመር ፡ እርሱ ፡ አስቦአልና ፥
የድሆችንም ፡ ጩኸት ፡ አልረሳምና ።
፲፫ አቤቱ ፥ እዘንልኝ ፥ ጠላቶቼም ፡ የሚያመጡብኝን ፡ መከራ ፡ እይ ፥
ከሞት ፡ ደጆች ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ የምታደርገኝ ፤
፲፬ ምስጋናውን ፡ ሁሉ ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፤
በጽዮን ፡ ልጅ ፡ በደጆችዋ ፡
በማዳንህ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።
፲፭ አሕዛብ ፡ በሠሩት ፡ ጕድጓድ ፡ ወደቁ ፥
በዚያችም ፡ በሸሸጉት ፡ ወጥመድ ፡ እግራቸው ፡ ተጠመደች ።
፲፮ እግዚአብሔር ፡ ፍርድን ፡ በማድረግ ፡ የታወቀ ፡ ነው ፤
ኃጢአተኛው ፡ በእጆቹ ፡ ሥራ ፡ ተጠመደ ።
፲፯ ኃጢአተኞች ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ይመለሳሉ ፥
እግዚአብሔርን ፡ የሚረሱ ፡ አሕዛብም ፡ ሁሉ ።
፲፰ ድሀ ፡ ለዘላለም ፡ አይረሳምና ፥
የችግረኞችም ፡ ተስፋቸው ፡ ለዘላለም ፡ አይጠፋም ።
፲፱ አቤቱ ፥ ተነሥ ፤ ሰውም ፡ አይበርታ ፥
አሕዛብም ፡ በፊትህ ፡ ይፈረድባቸው ።
፳ አቤቱ ፥ ፍርሃትን ፡ በላያቸው ፡ ጫንባቸው ፤
አሕዛብ ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ይወቁ ።

### (መዝሙር ፡ ፲ ፡ በዕብራይስጥ ፡)

(፩)፳፩ አቤቱ ፥ ለምን ፡ ርቀህ ፡ ቆምህ ?
በመከራም ፡ ጊዜ ፡ ለምን ፡ ትሰወራለህ ?
(፪)፳፪ በኃጢአተኛ ፡ ትዕቢት ፡ ድሀ ፡ ይናደዳል ፤
በሰቡት ፡ ተንኰላቸው ፡ ተጠመዱ ።
(፫)፳፫ ኃጢአተኛ ፡ በነፍሱ ፡ ፈቃድ ፡ ይወደሳልና ፥
ዓመፀኛም ፡ ይበርከል ።
(፬)፳፬ ኃጢአተኛ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አበሳጨው ፥
እንደ ፡ ቍጣውም ፡ ብዛት ፡ አይመራመረውም ፤
በእርሱ ፡ ፊት ፡ እግዚአብሔር ፡ የለም ።
(፭)፳፭ መንገዱ ፡ ሁሉ ፡ የረከሰ ፡ ነው ፥
ፍርድህም ፡ በፊቱ ፡ የፈረሰ ፡ ነው ፥
ጠላቶችንም ፡ ሁሉ ፡ ይገዛቸዋል ።
(፮)፳፮ በልቡ ፡ ይላል ፡— ለልጅ ፡ ልጅ ፡ አልታወክም ፡ ክፉም ፡ አያገኘኝም ።
(፯)፳፯ አፉ ፡ መርገምንና ፡ ሽንገላን ፡ ተንኰልን ፡ የተመላ ፡ ነው ፤
ከምላሱ ፡ በታች ፡ ጉዳትና ፡ መከራ ፡ ነው ።
(፰)፳፰ በመንደሮች ፡ መሸመቂያ ፡ ይቀመጣል ፡
ንጹሐንን ፡ በስውር ፡ ይገድል ፡ ዘንድ ፤
ዓይኖቹም ፡ ወደ ፡ ድኃ ፡ ይመለከታሉ ።

(፱) ፳፱፤ እንደ ፡ አንበሳ ፡ በችፍግ ፡ ዱር ፡ በስውር ፡ ይሸምቃል ፤
ድሀውን ፡ ለመንጠቅ ፡ ያደባል ፤
ድሀውን ፡ ይነጥቀዋል ፡ በአሽክላውም ፡ ይስበዋል ።
(፲) ፴፤ ድሀ ፡ ይዋረዳል ፥ ይጐብጣል ፤
በኃያላኑም ፡ እጅ ፡ ይወድቃል ።
(፲፩) ፴፩፤ በልቡም ፡ ይላል ፡— እግዚአብሔር ፡ ረስቶኛል ፤
ፊጽሞም ፡ እንዳያይ ፡ ፊቱን ፡ ሰወረ ።
(፲፪) ፴፪፤ አቤቱ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ ተነሥ ፡ እጅህም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ትበል ፤
ድሆችን ፡ አትርሳ ።
(፲፫) ፴፫፤ ኃጢአተኛ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አስቈጣው ?
በልቡ ፡— አይመራመረኝም ፡ ይላልና ።
(፲፬) ፴፬፤ አየኸው ፥ አንተ ፡ ክፋትንና ፡ ቍጣን ፡ ትመለከታለህና ፥
በእጅህ ፡ ፍዳውን ፡ ለመስጠት ፤
ድሀ ፡ ራሱን ፡ ለአንተ ፡ ይተዋል ፥
ለድሀ ፡ አደግም ፡ ረዳቱ ፡ አንተ ፡ ነህ ።
(፲፭) ፴፭፤ የኃጢአተኛንና ፡ የክፉን ፡ ክንድ ፡ ሰበር ፥
የኃጢአቱንም ፡ ብድራት ፡ ክፈል ፡ ሌላ ፡ እስከ ማይገኝ ፡ ድረስ ።
(፲፮) ፴፮፤ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ይነግሣል ፤
አሕዛብ ፡ ከምድሩ ፡ ይጠፋሉ ።
(፲፯) ፴፯፤ እግዚአብሔር ፡ የድሆችን ፡ ምኞት ፡ ሰማ ፥
ጆሮውም ፡ የልባቸውን ፡ አሳብ ፡ አደመጠች ፥
(፲፰) ፴፰፤ ፍርዱ ፡ ለድሀ ፡ አደግና ፡ ለችግረኛ ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፥
ሰዎች ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አፋቸውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ማድረግ ፡ እንዳይደግሙ ።

## መዝሙር ፡ ፲ ፡ (፲፩)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ በእግዚአብሔር ፡ ታመንሁ ፤
ነፍሴን ፡— እንደ ፡ ወፍ ፡ ወደ ፡ ተራሮች ፡ ተቅበዝበዢ ፡ እንዴት ፡ ትሉአታላችሁ ?
፪፤ ኃጢአተኞች ፡ እነሆ ፡ ቀስታቸውን ፡ ገትረዋልና ፥
ፍላጻቸውንም ፡ በአውታር ፡ አዘጋጅተዋልና ፥
ልበ ፡ ቅኖችን ፡ በስውር ፡ ይነድፉ ፡ ዘንድ ።
፫፤ አንተ ፡ የሠራኸውን ፡ እነሆ ፡ እነርሱ ፡ አፍርሰዋልና ፤
ጻድቅ ፡ ግን ፡ ምን ፡ አደረገ ?
፬፤ እግዚአብሔር ፡ በተቀደሰው ፡ መቅደሱ ፡ ነው ፤
እግዚአብሔር ፥ ዙፋኑ ፡ በሰማይ ፡ ነው ፤
ዓይኖቹ ፡ ወደ ፡ ድሀ ፡ ይመለከታሉ ፥
ቅንድቦቹም ፡ የሰው ፡ ልጆችን ፡ ይመረምራሉ ።
፭፤ እግዚአብሔር ፡ ጻድቅንና ፡ ኀጥእን ፡ ይመረምራል ፤
ዓመፃን ፡ የወደዳት ፡ ግን ፡ ነፍሱን ፡ ጠልቶአል ።
፮፤ ወጥመድ ፡ በኀጥአን ፡ ላይ ፡ ያዘንባል ፡
እሳትና ፡ ዲን ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስም ፡ የጽዋቸው ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ ነው ።
፯፤ እግዚአብሔር ፡ ጻድቅ ፡ ነውና ፥ ጽድቅንም ፡ ይወድዳል ፤
ቅንነት ፡ ግን ፡ ፊቱን ፡ ታየዋለች ።

## መዝሙር ፡ ፲፩ ፡ (፲፪)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፥ ስለ ፡ ስምንተኛ ፤
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ፥ አድነኝ ፤ ደግ ፡ ሰው ፡ አልቆአልና ፥
ከሰው ፡ ልጆችም ፡ መተማመን ፡ ጐድሎአልና ።
፪፤ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ከንቱ ፡ ነገርን ፡ ይናገራሉ ፤
በሽንገላ ፡ ከንፈር ፡ ሁለት ፡ ልብ ፡ ሆነው ፡ ይናገራሉ ።
፫፤ የሽንገላን ፡ ከንፈሮች ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያጠፋቸዋል ፥
ታላቅ ፡ ነገርን ፡ የምትናገረውንም ፡ ምላስ ፤
፬፤ ምላሳችንን ፡ እናበረታለን ፤
ከንፈራችን ፡ የእኛ ፡ ነው ፥ ጌታችን ፡ ማን ፡ ነው ? የሚሉትን ።
፭፤ ስለ ፡ ድሆች ፡ መከራ ፥ ስለ ፡ ችግረኞች ፡ ጩኸት ፡
እግዚአብሔር ፡— አሁን ፡ እነሣለሁ ፡ ይላል ፤
መድኃኒትን ፡ አደርጋለሁ ፥ በላዩም ፡ እገልጣለሁ ።
፮፤ በምድር ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተፈተነ ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ተጣራ ፡ ብር ፡
የእግዚአብሔር ፡ ቃላት ፡ የነጹ ፡ ቃላት ፡ ናቸው ።
፯፤ አቤቱ ፥ አንተ ፡ ጠብቀን ፥
ከዚህችም ፡ ትውልድ ፡ ለዘላለም ፡ ታደገን ።
፰፤ በሰው ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ ምናምንቴ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡
ክፉዎች ፡ በዙሪያው ፡ ሁሉ ፡ ይመላለሳሉ ።

## መዝሙር ፡ ፲፪ ፡ (፲፫)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ፥ እስከ ፡ መቼ ፡ ፈጽመህ ፡ ትረሳኛለህ ?
እስከ ፡ መቼስ ፡ ፊትህን ፡ ከእኔ ፡ ትሰውራለህ ?
፪፤ እስከ ፡ መቼ ፡ በነፍሴ ፡ እመክከራለሁ ?
ትካዜስ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ሁልጊዜ ፡ ይሆናል ?
እስከ ፡ መቼ ፡ ጠላቴ ፡ በላዬ ፡ ይጓደዳል ?
፫፤ አቤቱ ፡ አምላኬ ፥ እየኝ ፡ ስማኝም ፤
ጠላቴ ፡— አሸነፍሁት ፡ እንዳይል ፥
፬፤ የሚያስጨንቁኝም ፡ እኔ ፡ ብናወጥ ፡ ደስ ፡ እንዳይላቸው ፥
ለሞትም ፡ እንዳልተኛ ፡ ዓይኖቼን ፡ አብራ ።
፭፤ እኔ ፡ ግን ፡ በቸርነትህ ፡ ታመንሁ ፥
ልቤም ፡ በመድኃኒትህ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።
፮፤ የረዳኝን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግናለሁ ፥
ለልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ ስምም ፡ እዘምራለሁ ።

## መዝሙር ፡ ፲፫ ፡ (፲፬)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ ሰነፍ ፡ በልቡ ፡— አምላክ ፡ የለም ፡ ይላል ።
በሥራቸው ፡ ረከሱ ፥ ጐሰቈሉ ፤
በጎ ፡ ነገርን ፡ የሚሠራ ፡ የለም ።

፪፤ የሚያስተውል ፡ እግዚአብሔርንም ፡ የሚፈ
ልግ ፡ እንዳለ ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡
እግዚአብሔር ፡ ከሰማይ ፡ የሰው ፡ ልጆችን ፡
ተመለከተ ።
፫፤ ሁሉ ፡ ዐመፁ ፡ በአንድነትም ፡ ረከሱ ፤
በጎ ፡ ነገርን ፡ የሚሠራ ፡ የለም ፤ አንድም ፡ ስንኳ ፡
የለም ።
፬፤ ጕሮሮአቸው ፡ የተከፈተ ፡ መቃብር ፡ ነው ፥
በምላሳቸው ፡ ሸነገሉ ፤
፭፤ ከከንፈራቸው ፡ በታች ፡ የእባብ ፡ መርዝ ፡ አለ ፤
አፋቸው ፡ መርገምንና ፡ መራራን ፡ ተሞልቶ
አል ፤
፮፤ ደምን ፡ ለማፍሰስ ፡ እግራቸው ፡ ፈጣን ፡ ነው ፤
ጥፋትና ፡ ጕስቍልና ፡ በመንገዳቸው ፡ አለ ፥
የሰላምን ፡ መንገድ ፡ አላወቁአትምና ፤
እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ በዓይናቸው ፡ ፊት ፡
የለም ።
፯፤ ሕዝቤን ፡ እንደ ፡ እንጀራ ፡ የሚበሉ ፡
ኃጢአት ፡ የሚሠሩ ፡ ሁሉ ፡ በውኑ ፡ አያውቁ
ምን ?
እግዚአብሔርንም ፡ አይጠሩትም ።
፰፤ በዚያ ፡ በታላቅ ፡ ፍርሃት ፡ እጅግ ፡ ፈሩ ፥
እግዚአብሔር ፡ በጻድቃን ፡ ትውልድ ፡ ዘንድ ፡
ነውና ።
፱፤ የድሆችን ፡ ምክር ፡ አሳፈራችሁ ፥
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ተስፋቸው ፡ ነው ።
፲፤ ከጽዮን ፡ መድኀኒትን ፡ ለእስራኤል ፡ ማን ፡ ይሰ
ጣል ?
እግዚአብሔር ፡ የሕዝቡን ፡ ምርኮ ፡ በመለሰ ፡
ጊዜ ፥
ያዕቆብ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፥ እስራኤልም ፡ ሐሤት ፡
ያደርጋል ።

## መዝሙር ፡ ፲፬ ፡ (፲፭)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ፥ በድንኳንህ ፡ ውስጥ ፡ ማን ፡ ያድራል ?
በተቀደሰውም ፡ ተራራህ ፡ ማን ፡ ይኖራል ?
፪፤ በቅንነት ፡ የሚሄድ ፥ ጽድቅንም ፡ የሚያደርግ ፥
በልቡም ፡ እውነትን ፡ የሚናገር ።
፫፤ በአንደበቱ ፡ የማይሸነግል ፥
በባልንጀራው ፡ ላይ ፡ ክፋትን ፡ የማያደርግ ፥
ዘመዶቹንም ፡ የማይሰድብ ።
፬፤ ኃጢአተኛ ፡ በፊቱ ፡ የተናቀ ፥
እግዚአብሔርንም ፡ የሚፈሩትን ፡ የሚያከብር ፥
ለባልንጀራው ፡ የሚምል ፡ የማይከዳም ።
፭፤ ገንዘቡን ፡ በአራጣ ፡ የማያበድር ፥
በንጹሑ ፡ ላይ ፡ መማለጃን ፡ የማይቀበል ።
እንዲህ ፡ የሚያደርግ ፡ ለዘላለም ፡ አይታወ
ክም ።

## መዝሙር ፡ ፲፭ ፡ (፲፮)

የዳዊት ፡ ቅኔ ።

፩፤ አቤቱ ፥ በአንተ ፡ ታምኜለሁና ፡ ጠብቀኝ ።
፪፤ እግዚአብሔርን ፡— አንተ ፡ ጌታዬ ፡ ነህ ፡ አልሁ ፤
ከአንተ ፡ በቀር ፡ በጎነት ፡ የለኝም ።
፫፤ ፈቃድህ ፡ ሁሉ ፡ በምድር ፡ በሉት ፡ ቅዱሳንና ፡
ክቡራን ፡ ላይ ፡ ነው ።
፬፤ ወደ ፡ ሌላ ፡ ለሚፋጠኑት ፡ መከራቸው ፡ ይበዛል ፤
የቍርባናቸውን ፡ ደም ፡ እኔ ፡ አላፈስሰውም ፥
ስማቸውንም ፡ በከንፈሬ ፡ አልጠራም ።
፭፤ እግዚአብሔር ፡ የርስቴ ፡ እድል ፡ ፈንታና ፡
ጽዋዬ ፡ ነው ፥
ዕጣዬንም ፡ የምታጠና ፡ አንተ ፡ ነህ ።
፮፤ ገመድ ፡ በማረ ፡ ስፍራ ፡ ወደቀችልኝ ፥
ርስቴም ፡ ተዋበችልኝ ።
፯፤ የመከረኝን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እባርካለሁ ፤
ደግሞም ፡ በሌሊት ፡ ኵላሊቶቼ ፡ ይገሥጹኛል ።
፰፤ ሁልጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በፊቴ ፡ አየዋለሁ ፤
በቀኜ ፡ ነውና ፡ አልታወክም ።
፱፤ ስለዚህ ፡ ልቤን ፡ ደስ ፡ አለው ፡
ምላሴም ፡ሐሤት ፡ አደረገች ፤
ሥጋዬ ፡ ደግሞ ፡ በተስፋ ፡ ታድራለች ፤
፲፤ ነፍሴን ፡ በሲኦል ፡ አትተዋትምና ፥
ቅዱስህንም ፡ መበስበስን ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ አትተ
ወውም ።
፲፩፤ የሕይወትን ፡ መንገድ ፡ አሳየኸኝ ፤
ከፊትህ ፡ ጋር ፡ ደስታን ፡ አጠገብኸኝ ፥
በቀኝህም ፡ የዘላለም ፡ ፍሥሐ ፡ አለ ።

## መዝሙር ፡ ፲፮ ፡ (፲፯)

የዳዊት ፡ ጸሎት ።

፩፤ አቤቱ ፥ ጽድቄን ፡ ስማ ፡ ጩኸቴንም ፡ አድምጥ ፤
በተንኰለኛም ፡ ከንፈር ፡ ያልሆነውን ፡ ጸሎቴን ፡
አድምጥ ።
፪፤ ፍርዴ ፡ ከፊትህ ፡ ይውጣ ፥
ዓይኖችህም ፡ በቅንነት ፡ ይዩ ።
፫፤ ልቤን ፡ ፈተንኸው ፡ በሌሊትም ፡ ጐበኘኸኝ ፤
ፈተንኸኝ ፥ ምንም ፡ አላገኘህብኝም ።
፬፤ የሰውን ፡ ሥራ ፡ አፌ ፡ እንዳይናገር ፡ ፈቃዴ ፡
ነው ፤
ስለ ፡ ከንፈሮችህ ፡ ቃል ፡ጭንቅ ፡ የሆኑ ፡ መንገ
ዶችን ፡ ጠበቅሁ ።
፭፤ እግሮች ፡ እንዳይናወጡ ፡ አረማመዴን ፡ በመን
ገድህ ፡ አጽና ።
፮፤ አቤቱ ፥ ሰምተኸኛልና ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ጠራሁ ፤
ጆሮህን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አዘንብል ፥ ቃሌንም ፡ ስማ ።
፯፤ የሚያምኑህን ፡ ከሚቃወሙ ፡ በቀኝህ ፡ የምታ
ድናቸው ፥
ቸርነትህን ፡ ድንቅ ፡ አድርገህ ፡ ግለጠው ።
፰፤ እንደ ፡ ዓይን ፡ ብሌን ፡ ጠብቀኝ ፥
በክንፎችህ ፡ ጥላ ፡ ሰውረኝ ፡
፱፤ ከሚያስጨንቁኝ ፡ ከኃጢአተኞች ፥
ነፍሴንም ፡ ከሚከብቡአት ፡ ከጠላቶቼ ።
፲፤ አንጀታቸውን ፡ በስብ ፡ ቋጠሩ ፥
በአፋቸውም ፡ ትዕቢትን ፡ ተናገሩ ።
፲፩፤ አሁንም ፡ እርምጃችንን ፡ ከበቡ ፤
ዓይናቸውን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አደረጉ ።
፲፪፤ እርሱ ፡ ንጥቂያን ፡ እንደሚናፍቅ ፡ አንበሳ ፡

ተሸጕጦም ፡ እንደሚኖር ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡
ደቦል ፡ ነው ።
፲፫ ፡ አቤቱ ፥ ተነሥ ፤ ቀድመህ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ ጣለው ፤
ነፍሴን ፡ ከኃጢአተኛ ፡ በሰይፍህ ፡ አድናት ።
፲፬ ፡ አቤቱ ፥ ከሰዎች ፥
እድል ፡ ፈንታቸው ፡ በሕይወታቸው ፡ ከሆነች ፡
ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ሰዎች ፡ በእጅህ ፡ አድነኝ ፤
ከሰወርኸው ፡ መዝገብህ ፡ ሆዳቸውን ፡ አጠገብህ ፤
ልጆቻቸው ፡ ብዙ ፡ ናቸው ፡
የተረፋቸውንም ፡ ለሕፃናቶቻቸው ፡ ያተርፋሉ ።
፲፭ ፡ እኔ ፡ ግን ፡ በጽድቅ ፡ ፊትህን ፡ አያለሁ ፤
ክብርህን ፡ ሳይ ፡ እጠግባለሁ ።

## መዝሙር ፡ ፲፯ ፡ (፲፰ ፡ )

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ ከሳኦል ፡ እጅና ፡ ከጠላቶቹ ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ እግዚአብሔር ፡ ባዳነው ፡ ቀን ፡ በዚህ ፡ መዝሙር ፡ ቃል ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተናገረው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡ የዳዊት ፡ መዝሙር ። እንዲህም ፡ አለ ፡—

፩ ፡ አቤቱ ፡ ጕልበቴ ፡ ሆይ ፥ እወድድሃለሁ ።
፪ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዓለቴ ፥ አምባዬ ፥ መድኃኒቴ ፥
አምላኬ ፥ በእርሱም ፡ የምተማመንበት ፡ ረዳቴ ፥
መታመኛዬና ፡ የደኅንነቴ ፡ ቀንድ ፡ መጠጊያ
ዬም ፡ ነው ።
፫ ፡ ምስጋና ፡ የሚገባውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እጠ
ራለሁ ፥
ከጠላቶቼም ፡ እድናለሁ ።
፬ ፡ የሞት ፡ ጣር ፡ ያዘኝ ፥
የዓመፅ ፡ ፈሳሽም ፡ አስፈራኝ ፤
፭ ፡ የሲኦል ፡ ጣር ፡ ከበበኝ ፤
የሞት ፡ ወጥመድም ፡ ደረሰብኝ ።
፮ ፡ በጨነቀኝ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠራሁት ፥
ወደ ፡ አምላኬም ፡ ጮኽሁ ፤
ከመቅደሱም ፡ ቃሌን ፡ ሰማኝ ፥
ጩኸቴም ፡ በፊቱ ፡ ወደ ፡ ጆሮው ፡ ገባ ።
፯ ፡ ምድርም ፡ ተንቀጠቀጠች ፡ ተናወጠችም ፥
የተራሮችም ፡ መሠረቶች ፡ ተነቃነቁ ፥
እግዚአብሔርም ፡ ተቈጥቶአልና ፡ ተንቀጠ
ቀጡ ።
፰ ፡ ከቍጣው ፡ ጢስ ፡ ወጣ ፥ ከፊቱም ፡ የሚበላ ፡
እሳት ፡ ነደደ ፤
ፍምም ፡ ከእርሱ ፡ በራ ።
፱ ፡ ሰማዮችን ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አደረገ ፡ ወረደም ፥
ጨለማ ፡ ከእግሩ ፡ በታች ፡ ነበረ ።
፲ ፡ በኪሩቤልም ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ በረረ ፥
በነፋስም ፡ ክንፍ ፡ በረረ ።
፲፩ ፡ መሰወሪያውን ፡ ጨለማ ፡ አደረገ ፤
በዙሪያውም ፡ ድንኳኑ ፤
በደመናት ፡ ውስጥ ፡ የጨለማ ፡ ውኃ ፡ ነበረ ።
፲፪ ፡ በፊቱ ፡ ካለው ፡ ብርሃን ፡ የተነሣ ፡ ደመናትና ፡
በረዶ ፡
የእሳት ፡ ፍምም ፡ አለፉ ።
፲፫ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ከሰማያት ፡ አንጐደጐደ ፥
ልዑልም ፡ ቃሉን ፡ ሰጠ ።
፲፬ ፡ ፍላጻውን ፡ ላከ ፡ በተናቸውም ፤
መብረቆችን ፡ አበዛ ፡ አወካቸውም ።
፲፭ ፡ አቤቱ ፥ ከዘለፋህ ፡
ከመዓትህም ፡ መንፈስ ፡ እስትንፋስ ፡ የተነሣ ፥
የውኆች ፡ ምንጮች ፡ ታዩ ፥
የዓለም ፡ መሠረቶችም ፡ ተገለጡ ።
፲፮ ፡ ከላይ ፡ ሰደደ ፡ ወሰደኝም ፥
ከብዙ ፡ ውኆችም ፡ አወጣኝ ።
፲፯ ፡ ከብርቱዎች ፡ ጠላቶቼ ፡
ከሚጠሉኝም ፡ አዳነኝ ፥ በርትተውብኝ ፡ ነበርና ።
፲፰ ፡ በመከራዬ ፡ ቀን ፡ ደረሱብኝ ፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ደገፋዬ ፡ ሆነ ።
፲፱ ፡ ወደ ፡ ሰፊ ፡ ስፍራም ፡ አወጣኝ ፤
ወድዶኛልና ፡ አዳነኝ ።
፳ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ጽድቄ ፡ ይከፍለኛል ፤
እንደ ፡ እጄ ፡ ንጽሕና ፡ ይመልስልኛል ።
፳፩ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንገድ ፡ ጠብቄአለሁና ፥
በአምላኬም ፡ አላመፅሁም ።
፳፪ ፡ ፍርዱ ፡ ሁሉ ፡ በፊቴ ፡ ነበረና ፥
ሥርዓቱንም ፡ ከፊቴ ፡ አላራቅሁም ።
፳፫ ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ቅን ፡ ነበርሁ ፥
ከኃጢአቴም ፡ ተጠበቅሁ ።
፳፬ ፡ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ጽድቄ ፡
እንደ ፡ እጄም ፡ ንጽሕና ፡ በዓይኖቹ ፡ ፊት ፡ መለ
ሰልኝ ።
፳፭ ፡ ከቸር ፡ ሰው ፡ ጋር ፡ ቸር ፡ ሆነህ ፡ ትገኛለህ ፤
ከቅን ፡ ሰው ፡ ጋር ፡ ቅን ፡ ሆነህ ፡ ትገኛለህ ፤
፳፮ ፡ ከንጹሕ ፡ ጋር ፡ ንጹሕ ፡ ሆነህ ፡ ትገኛለህ ፤
ከጠማማም ፡ ጋር ፡ ጠማማ ፡ ሆነህ ፡ ትገኛለህ ።
፳፯ ፡ አንተ ፡ የተጠቃውን ፡ ሕዝብ ፡ ታድናለህና ፥
የትዕቢተኞችን ፡ ዓይን ፡ ግን ፡ ታዋርዳለህ ።
፳፰ ፡ አንተ ፡ መብራቴን ፡ ታበራለህና ፤
እግዚአብሔር ፡ አምላኬ ፡ ጨለማዬን ፡ ያበራል ።
፳፱ ፡ በአንተ ፡ ከጥፋት ፡ እድናለሁና ፥
በአምላኬም ፡ ቅጥሩን ፡ እዘልላለሁ ።
፴ ፡ የአምላኬ ፡ መንገድ ፡ ፍጹም ፡ ነው ፥
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ የነጠረ ፡ ነው ፥
በእርሱ ፡ ለሚታመኑት ፡ ሁሉ ፡ ጋሻ ፡ ነው ።
፴፩ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በቀር ፡ አምላክ ፡ ማን ፡ ነው ?
ከአምላካችን ፡ በቀር ፡ አምላክ ፡ ማን ፡ ነው ?
፴፪ ፡ ኃይልን ፡ የሚያስታጥቀኝ ፡ መንገዴንም ፡ የሚ
ያቃና ፥
፴፫ ፡ እግሮቼን ፡ እንደ ፡ ብሖር ፡ እግሮች ፡ የሚያረታ ፡
በኮረብቶችም ፡ የሚያቆመኝ ፡ እግዚአብሔር ፡
ነው ።
፴፬ ፡ እጆቼን ፡ ሰልፍ ፡ ያስተምራል ፥
በክንዴም ፡ የናስ ፡ ቀስት ፡ እገትራለሁ ።
፴፭ ፡ ለደኅንነቴም ፡ መታመኛን ፡ ሰጠኸኝ ፥
ቀኝህም ፡ ትረዳኛለች ፥
ትምህርትህም ፡ ለዘላለም ፡ ታጠናኛለች ፥
ተግሣጽህም ፡ ታስተምረኛለች ።
፴፮ ፡ አረማመዴን ፡ በበታቼ ፡ አሰፋህ ፥
እግሮቼም ፡ አልተንሸራተቱም ።
፴፯ ፡ ጠላቶቼን ፡ አሳድዳቸዋለሁ ፡ እይዛቸዋለሁም ፥

እስከጠፉቸውም ፡ ድረስ ፡ አልመለስም ።
፴፰ እስጨንቃቸዋለሁ ፡ መቆምም ፡ አይችሉም ፥
ከእግሬም ፡ በታች ፡ ይወድቃሉ ።
፴፱ ለሰልፍም ፡ ኃይልን ፡ ታስታጥቀኛለህ ፤
በበላዬ ፡ የቆሙትን ፡ ሁሉ ፡ በበታቼ ፡ ታስገዛቸዋለህ ።
፵ የጠላቶቼን ፡ ጀርባ ፡ ሰጠኸኝ ፥
የሚጠሉኝንም ፡ አጠፋሃቸው ።
፵፩ ጮኹ ፡ የሚረዳቸውም ፡ አልነበረም ፤
ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ጮኹ ፡ አልሰማቸውም ።
፵፪ እንደ ፡ ትቢያ ፡ በነፋስ ፡ ፊት ፡ እፈጫቸዋለሁ ፥
እንደ ፡ አደባባይም ፡ ጭቃ ፡ እረግጣቸዋለሁ ።
፵፫ ከሕዝብ ፡ ክርክር ፡ ታድነኛለህ ፥
የአሕዛብም ፡ ራስ ፡ አድርገህ ፡ ትሾመኛለህ ፥
የማላውቀው ፡ ሕዝብም ፡ ይገዛልኛል ።
፵፬ በጆሮ ፡ ሰምተው ፡ ተገዙልኝ ፤
የባዕድ ፡ ልጆች ፡ ደለሉኝ ።
፵፭ የባዕድ ፡ ልጆች ፡ አረጁ ፥
በመንገዳቸውም ፡ ተሰናከሉ ።
፵፮ እግዚአብሔር ፡ ሕያው ፡ ነው ፥ አምላኬም ፡ ቡሩክ ፡ ነው ፥
የመድኃኒቴም ፡ አምላክ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይበል ።
፵፯ በቀሌን ፡ የሚመልስልኝ ፡ አምላክ ፡
አሕዛብን ፡ በበታቼ ፡ ያስገዛልኛል ።
፵፰ ከጠላቶቼ ፡ የሚታደገኝ ፡ እርሱ ፡ ነው ፤
በእኔም ፡ ላይ ፡ ከቆሙ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ታደርገኛለህ ፥
ከግፈኛ ፡ ሰው ፡ ታድነኛለህ ።
፵፱ አቤቱ ፥ ስለዚህ ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ አመሰግንሃለሁ ፥
ለስምህም ፡ እዘምራለሁ ።
፶ የንጉሡን ፡ መድኃኒት ፡ ታላቅ ፡ ያደርጋል ፥
ቸርነቱንም ፡ ለቀባው ፡ ለዳዊትና ፡ ለዘሩ ፡ ለዘላለም ፡ ይሰጣል ።

## መዝሙር ፡ ፲፰ ፡ (፲፱)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፡ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ ሰማያት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ክብር ፡ ይናገራሉ ፥
የሰማይም ፡ ጠፈር ፡ የእጁን ፡ ሥራ ፡ ያወራል ።
፪ ቀን ፡ ለቀን ፡ ነገርን ፡ ታወጣለች ፥
ሌሊትም ፡ ለሌሊት ፡ እውቀትን ፡ ትናገራለች ።
፫ ነገር ፡ የለም ፡ መናገርም ፡ የለም ፥
ድምፃቸውም ፡ አይሰማም ።
፬ ድምፃቸው ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፥
ቃላቸውም ፡ እስከ ፡ ዓለም ፡ ዳርቻ ፡ ወጣ ።
፭ በእነርሱም ፡ ውስጥ ፡ የፀሐይን ፡ ድንኳን ፡ አደረገ ፥
እርሱም ፡ እንደ ፡ ሙሽራ ፡ ከእልፍኙ ፡ ይወጣል ፤
እንደ ፡ አርበኛ ፡ በመንገዱ ፡ ለመሮጥ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።
፮ አወጣጡ ፡ ከሰማያት ፡ ዳርቻ ፡ ነው ፥
ዙረቱም ፡ እስከ ፡ ዳርቻቸው ፡ ነው ፤
ከትኩሳቱም ፡ የሚሰወር ፡ የለም ።
፯ የእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ፍጹም ፡ ነው ፤ ነፍስን ፡ ይመልሳል ፤
የእግዚአብሔር ፡ ምስክር ፡ የታመነ ፡ ነው ፤ ሕፃናትን ፡ ጠቢባን ፡ ያደርጋል ።
፰ የእግዚአብሔር ፡ ሥርዓት ፡ ቅን ፡ ነው ፥ ልብንም ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፤
የእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ ብሩህ ፡ ነው ፥ ዓይንንም ፡ ያበራል ።
፱ የእግዚአብሔር ፡ ፍርሃት ፡ ንጹሕ ፡ ነው ፤ ለዘላለም ፡ ይኖራል ፤
የእግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ እውነትና ፡ ቅንነት ፡ በአንድነት ፡ ነው ።
፲ ከወርቅና ፡ ከክቡር ፡ ዕንቍ ፡ ይልቅ ፡ ይወደዳል ፤
ከማርና ፡ ከማር ፡ ወለላም ፡ ይጣፍጣል ።
፲፩ ባሪያህ ፡ ደግሞ ፡ ይጠብቀዋል ፤
በመጠበቁም ፡ እጅግ ፡ ይጠቀማል ።
፲፪ ስሕተትን ፡ ማን ፡ ያስተውላታል ?
ከተሰወረ ፡ ኃጢአት ፡ አንጻኝ ።
፲፫ የድፍረት ፡ ኃጢአት ፡ እንዳይገዛኝ ፡ ባሪያህን ፡ ጠብቅ ፤
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ፍጹም ፡ እሆናለሁ ፥
ከታላቁም ፡ ኃጢአት ፡ እነጻለሁ ።
፲፬ አቤቱ ፥ ረድኤቴ ፡ መድኃኒቴም ፥
የአፌ ፡ ቃልና ፡ የልቤ ፡ አሳብ ፡
በፊትህ ፡ ያማረ ፡ ይሁን ።

## መዝሙር ፡ ፲፱ ። (፳)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ በመከራ ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ ይስማህ ፤
የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ስም ፡ ያቁምህ ።
፪ ከመቅደሱ ፡ ረድኤትን ፡ ይላክልህ ፥
ከጽዮንም ፡ ያጥናህ ።
፫ ቍርባንህን ፡ ሁሉ ፡ ያስብልህ ፤
የሚቃጠል ፡ መሥዋዕትህን ፡ ያለምልምልህ ።
፬ እንደ ፡ ልብህ ፡ ይስጥህ ፥
ፈቃድህንም ፡ ሁሉ ፡ ይፈጽምልህ ።
፭ በማዳንህ ፡ ደስ ፡ ይለናል ፤
በአምላካችን ፡ ስም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እንላለን ፤
ልመናህን ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይፈጽምልህ ።
፮ እግዚአብሔር ፡ የቀባውን ፡ እንዳዳነው ፡ ዛሬ ፡ አወቅሁ ፤
ከሰማይ ፡ መቅደሱ ፡ ይመልስለታል ፡
በቀኙ ፡ ብርታት ፡ ማዳን ።
፯ እነዚያ ፡ በሰረገላ ፡ እነዚያም ፡ በፈረስ ፡ ይታመናሉ ፤
እኛ ፡ ግን ፡ በአምላካችን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እንላለን ።
፰ እነርሱ ፡ ተሰነካከለው ፡ ወደቁ ፤
እኛ ፡ ግን ፡ ተነሣን ፥ ጸንተንም ፡ ቆምን ።
፱ አቤቱ ፥ ንጉሥን ፡ አድነው ፥
በጠራንህም ፡ ቀን ፡ ስማን ።

## መዝሙር ፡ ፳ ። (፳፩)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ፥ በኃይልህ ፡ ንጉሥ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤
በማዳንህ ፡ እጅግ ፡ ሐሤትን ፡ ያደርጋል ።

፪ ፤ የልቡን ፡ ፈቃድ ፡ ሰጠኸው ፥
የከንፈሩንም ፡ ልመና ፡ አልከለከልኸውም ።
፫ ፤ በበጎ ፡ በረከት ፡ ደርሰህለታልና ፤
ከክቡር ፡ ዕንቍ ፡ የሆነ ፡ ዘውድን ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ አኖርህ ።
፬ ፤ ሕይወትን ፡ ለመነህ ፡ ሰጠኸውም ፥
ለረጅም ፡ ዘመን ፡ ለዘላለሙ ።
፭ ፤ በማዳንህ ፡ ክብሩ ፡ ታላቅ ፡ ነው ፤
ክብርንና ፡ ምስጋናን ፡ ጨመርህለት ።
፮ ፤ የዘላለም ፡ በረከትን ፡ ሰጥተኸዋልና ፥
በፊትህም ፡ ደስታ ፡ ደስ ፡ ታሰኘዋለህ ።
፯ ፤ ንጉሥ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ተማምኖአልና ፥
በልዑልም ፡ ምሕረት ፡ አይናወጥም ።
፰ ፤ እጅህ ፡ ጠላቶችህን ፡ ሁሉ ፡ ታገኛቸው ፥
ቀኝህም ፡ የሚጠሉህን ፡ ሁሉ ፡ ታገኛቸው ።
፱ ፤ በተቈጣህም ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ እቶን ፡ አድርጋቸው ፤
እግዚአብሔር ፡ በቍጣው ፡ ያጠፋቸዋል ፥
እሳትም ፡ ትበላቸዋለች ።
፲ ፤ ፍሬአቸውን ፡ ከምድር ፡
ዘራቸውንም ፡ ከሰው ፡ ልጆች ፡ ታጠፋለህ ።
፲፩ ፤ ክፋትን ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ዘርግተዋልና ፥
የማይቻላቸውንም ፡ ምክር ፡ አሰቡ ።
፲፪ ፤ ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ትመልሳቸዋለህ ፤
ፍላጻን ፡ በፊታቸው ፡ ላይ ፡ ታዘጋጃለህ ።
፲፫ ፤ አቤቱ ፥ በኃይልህ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በል ፤
ጽናትህንም ፡ እናመሰግናለን ፡ እንዘምርማለን ።

## መዝሙር ፡ ፳፩ ። (፳፪)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፡ ስለ ፡ ንጋት ፡ ኃይል ፤
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ ፤ አምላኬ ፥ አምላኬ ፥ ለምን ፡ ተውኸኝ ?
እኔን ፡ ከማዳንና ፡ ከጩኸቴ ፡ ቃል ፡ ሩቅ ፡ ነህ ።
፪ ፤ አምላኬ ፥ በቀን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እጠራለሁ ፥ አልመለስህልኝም ፤
በሌሊትም ፡ እንኳ ፡ ዕረፍት ፡ የለኝም ።
፫ ፤ በእስራኤል ፡ የተመሰገንህ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ በቅድስና ፡ ትኖራለህ ።
፬ ፤ አባቶቻችን ፡ አንተን ፡ ተማመኑ ፥
ተማመኑ ፡ አንተም ፡ አዳንሃቸው ።
፭ ፤ ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኹ ፡ አመለጡም ፥
አንተንም ፡ ተማመኑ ፡ አላፈሩም ።
፮ ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ትል ፡ ነኝ ፡ ሰውም ፡ አይደለሁም ፤
የሰው ፡ ማላገጫ ፡ በሕዝብም ፡ ዘንድ ፡ የተናቅሁ ፡ ነኝ ።
፯ ፤ የሚያዩኝ ፡ ሁሉ ፡ ይላገዱብኛል ፤
ራሳቸውን ፡ እየነቀነቁ ፡ በከንፈሮቻቸው ፡ እንዲህ ፡ ይላሉ ፡—
፰ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ተማመነ ፥
እርሱንም ፡ ያድነው ፤
ቢወድደውስ ፡ ያድነው ።
፱ ፤ አንተ ፡ ግን ፡ ከሆድ ፡ አውጥተኸኛልና ፥
በእናቴ ፡ ጡት ፡ ሳለሁም ፡ በአንተ ፡ ታመንሁ ።
፲ ፤ ከማኅፀን ፡ ጀምሮ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ተጣልሁ ፤
ከእናቴ ፡ ሆድ ፡ ጀምረህ ፡ አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነህ ።
፲፩ ፤ ጭንቀት ፡ ቀርባለችና ፥
የሚረዳኝም ፡ የለምና ፡ ከእኔ ፡ አትራቅ ።
፲፪ ፤ ብዙ ፡ በሬዎች ፡ ከበቡኝ ፥
የሰቡትም ፡ ፍሪዳዎች ፡ ያዙኝ ፤
፲፫ ፤ እንደ ፡ ነጣቂና ፡ እንደሚጮኽ ፡ አንበሳ ፡
በላዬ ፡ አፋቸውን ፡ ከፈቱ ።
፲፬ ፤ እንደ ፡ ውኃ ፡ ፈሰስሁ ፡
አጥንቶቼም ፡ ሁሉ ፡ ተለያዩ ፤
ልቤ ፡ እንደ ፡ ሰም ፡ ሆነ ፥
በአንጀቴም ፡ መካከል ፡ ቀለጠ ።
፲፭ ፤ ኃይሌ ፡ እንደ ፡ ገል ፡ ደረቀ ፥
በጕሮሮዬም ፡ ምላሴ ፡ ተጣጋ ፥
ወደ ፡ ሞትም ፡ አሸዋ ፡ አወረድኸኝ ።
፲፮ ፤ ብዙ ፡ ውሾች ፡ ከብበውኛልና ፤
የክፉተኞች ፡ ጉባኤም ፡ ያዘኝ ፤
እጆቼንና ፡ እግሮቼን ፡ ቸነከሩኝ ።
፲፯ ፤ አጥንቶቼ ፡ ሁሉ ፡ ተቈጠሩ ፤
እነርሱም ፡ አዩኝ ፡ ተመለከቱኝም ።
፲፰ ፤ ልብሶቼን ፡ ለራሳቸው ፡ ተከፋፈሉ ፥
በቀሚሴም ፡ ላይ ፡ ዕጣ ፡ ተጣጣሉ ።
፲፱ ፤ አንተ ፡ ግን ፥ አቤቱ ፥ ከእኔ ፡ አትራቅ ፤
አንተ ፡ ጕልበቴ ፥ እኔን ፡ ለመርዳት ፡ ፍጠን ።
፳ ፤ ነፍሴን ፡ ከሰይፍ ፡ አድናት ፥
ብቻነቴንም ፡ ከውሾች ፡ እጅ ።
፳፩ ፤ ከአንበሳ ፡ አፍ ፡ አድነኝ ፥
ብቻነቴንም ፡ አንድ ፡ ቀንድ ፡ ካላቸው ።
፳፪ ፤ ስምህን ፡ ለወንድሞቼ ፡ እነግራቸዋለሁ ፥
በጉባኤም ፡ መካከል ፡ አመሰግንሃለሁ ።
፳፫ ፤ እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩ ፥ አመስግኑት ፤
የያዕቆብ ፡ ዘር ፡ ሁላችሁ ፥ አክብሩት ፥
የእስራኤልም ፡ ዘር ፡ ሁላችሁ ፥ ፍሩት ።
፳፬ ፤ የችግረኛን ፡ ችግር ፡ አልናቀምና ፥ ቸልም ፡ አላለምና ፤
ፊቱንም ፡ ከእኔ ፡ አልሰወረምና ፥
ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ በጮኽሁ ፡ ጊዜ ፡ ሰማኝ ።
፳፭ ፤ በታላቅ ፡ ጉባኤ ፡ ምስጋናዬ ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤
እርሱን ፡ በሚፈሩት ፡ ፊት ፡ ስእለቴን ፡ እሰጣለሁ ።
፳፮ ፤ ችግረኞች ፡ ይበላሉ ፥ ይጠግቡማል ፤
እግዚአብሔርንም ፡ የሚሹት ፡ ያመሰግኑታል ፤
ልባቸውም ፡ ለዘላለም ፡ ሕያው ፡ ይሆናል ።
፳፯ ፤ የምድር ፡ ዳርቻዎች ፡ ሁሉ ፡ ያስቡ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ይመለሱ ፤
የአሕዛብ ፡ ነገዶች ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ይሰግዳሉ ።
፳፰ ፤ መንግሥት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ነውና ፥
እርሱም ፡ አሕዛብን ፡ ይገዛል ።
፳፱ ፤ የምድር ፡ ደንዳኖች ፡ ሁሉ ፡ ይበላሉ ፡ ይሰግዳሉም ፤
ወደ ፡ መሬት ፡ የሚወርዱት ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ይንበረከካሉ ፤
ነፍሴም ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ በሕይወት ፡ ትኖራለች ።
፴ ፤ ዘሬ ፡ ይገዛለታል ፤

የምትመጣው ፡ ትውልድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ትነግረዋለች ፤

፴፩፤ ጽድቁንም ፡ ለሚወለደው ፡ ሕዝብ ÷
እግዚአብሔር ፡ ያደረገውን ፡ ጽድቁን ÷ ይነግራሉ።

## መዝሙር ፡ ፳፪ ። (፳፫)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ እረኛዬ ፡ ነው ÷ የሚያሳጣኝም ፡ የለም ።
፪፤ በለመለመ ፡ መስክ ፡ ያሳድረኛል ፤
በዕረፍት ፡ ውኃ ፡ ዘንድ ፡ ይመራኛል ።
፫፤ ነፍሴን ፡ መለሳት ÷
ስለ ፡ ስሙም ፡ በጽድቅ ፡ መንገድ ፡ መራኝ ።
፬፤ በሞት ፡ ጥላ ፡ መካከል ፡ እንኳ ፡ ብሄድ ፡
አንተ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ነህና ፡ ክፉን ፡ አልፈራም ፤
በትርህና ፡ ምርኵዝህ ፡ እነርሱ ፡ ያጸናኑኛል ።
፭፤ በፊቴ ፡ ገበታን ፡ አዘጋጀህልኝ ፡
በጠላቶቼ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፤
ራሴን ፡ በዘይት ፡ ቀባህ ÷
ጽዋዬም ፡ የተረፈ ፡ ነው ።
፮፤ ቸርነትህና ፡ ምሕረትህ ፡ በሕይወቴ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ይከተሉኛል ÷
በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ለዘላለም ፡ እኖራለሁ ።

## መዝሙር ፡ ፳፫ ። (፳፬)

በመጀመሪያ ፡ ሰንበት ፡ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ ምድርና ፡ ሞላዋ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ናት ÷
ዓለምም ፡ በእርስዋም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ።
፪፤ እርሱ ፡ በባሕሮች ፡ መሥርቶአታልና ÷
በፈሳሾችም ፡ አጽንቶአታልና ።
፫፤ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተራራ ፡ ማን ፡ ይወጣል ?
በቅድስናውስ ፡ ስፍራ ፡ ማን ፡ ይቆማል ?
፬፤ እጆቹ ፡ የነጹ ÷ ልቡም ፡ ንጹሕ ፡ የሆነ ÷
ነፍሱን ፡ ለከንቱ ፡ ያላነሣ ÷
ለባልንጀራውም ፡ በሽንገላ ፡ ያልማለ ።
፭፤ እርሱ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ በረከትን ፡
ከመድኃኒቱ ፡ አምላክም ፡ ምሕረትን ፡ ይቀበላል ።
፮፤ ይህች ፡ ትውልድ ፡ እርሱን ፡ የምትፈልግ ፡ ናት ÷
የያዕቆብን ፡ አምላክ ፡ ፊት ፡ የምትፈልግ ።
፯፤ እናንት ፡ መኳንንቶች ÷ በሮችን ፡ ክፈቱ ÷
የዘላለም ፡ ደጆችም ፡ ይከፈቱ ÷
የክብርም ፡ ንጉሥ ፡ ይግባ ።
፰፤ ይህ ፡ የክብር ፡ ንጉሥ ፡ ማን ፡ ነው ?
እግዚአብሔር ፡ ነው ÷ ብርቱና ፡ ኃያል ÷
እግዚአብሔር ፡ ነው ÷ በሰልፍ ፡ ኃያል ።
፱፤ እናንት ፡ መኳንንቶች ÷ በሮችን ፡ ክፈቱ ÷
የዘላለም ፡ ደጆችም ፡ ይከፈቱ ÷
የክብርም ፡ ንጉሥ ፡ ይግባ ።
፲፤ ይህ ፡ የክብር ፡ ንጉሥ ፡ ማን ፡ ነው ?
የጭፍሮች ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ÷
እርሱ ፡ የክብር ፡ ንጉሥ ፡ ነው ።

## መዝሙር ፡ ፳፬ ። (፳፭)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ÷ ወደ ፡ አንተ ፡ ነፍሴን ፡ አነሣለሁ ።
፪፤ አምላኬ ÷ አንተን ፡ ታመንሁ ፤ አልፈር ÷
ጠላቶቼ ፡ በእኔ ፡ አይሣቁብኝ ።
፫፤ አንተን ፡ ተስፋ ፡ የሚያደርጉ ፡ አያፍሩም ፤
በከንቱ ፡ የሚገበዙ ፡ ያፍራሉ ።
፬፤ አቤቱ ÷ መንገድህን ፡ አመልክተኝ ÷
ፍለጋህንም ፡ አስተምረኝ ።
፭፤ አንተ ፡ የመድኃኒቴ ፡ አምላክ ፡ ነህና ፡
በእውነትህ ፡ ምራኝ ÷ አስተምረኝም ፤
ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ አንተን ፡ ተስፋ ፡ አድርጌአለሁ ።
፮ አቤቱ ÷ ምሕረትህንና ፡ ቸርነትህን ፡ አስብ ÷
ከጥንት ፡ጀምሮ ፡ ናቸውና ።
፯፤ የልጅነቴን ፡ ኃጢአትና ፡ መተላለፍ ፡ አታስብብኝ ፤
አቤቱ ÷ ስለ ፡ ቸርነትህ ፡ ብዛት ፡ እንደ ፡ ምሕረትህ ፡ አስበኝ ።
፰፤ እግዚአብሔር ፡ ቸር ፡ ቅንም ፡ ነው ፤
ስለዚህ ፡ ኃጢአተኞችን ፡ በመንገድ ፡ ይመራቸዋል ።
፱፤ ገሮችን ፡ በፍርድ ፡ ይመራል ÷
ለገሮችም ፡ መንገድን ፡ ያስተምራቸዋል ።
፲፤ የእግዚአብሔር ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ ቸርነትና ፡ እውነት ፡ ነው ፡
ቃል ፡ ኪዳኑንና ፡ ምስክሩን ፡ ለሚጠብቁ ።
፲፩፤ አቤቱ ÷ ኃጢአቴ ፡ እጅግ ፡ ነውና ፡
ስለ ፡ ስምህ ፡ ይቅር ፡ በልኝ ።
፲፪፤ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰው ፡ ማን ፡ ነው ?
በሚመርጠው ፡ መንገድ ፡ ያስተምረዋል ።
፲፫፤ ነፍሱ ፡ በመልካም ፡ ታድራለች ÷
ዘሩም ፡ ምድርን ፡ ይወርሳል ።
፲፬፤ እግዚአብሔር ፡ ለሚፈሩት ፡ ኃይላቸው ፡ ነው ÷
ቃል ፡ ኪዳኑንም ፡ ያስታውቃቸዋል ።
፲፭፤ እርሱ ፡ እግሮቼን ፡ ከወጥመድ ፡ ያወጣቸዋልና ፡
ዓይኖቼ ፡ ሁልጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ናቸው ።
፲፮፤ እኔ ፡ ብቻዬንና ፡ ችግረኛ ፡ ነኝና ፡
ፊትህን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አድርግ ፡ ማረኝም ።
፲፯፤ የልቤ ፡ ችግር ፡ ብዙ ፡ ነው ፤
ከጭንቀቴ ፡ አውጣኝ ።
፲፰፤ ድካሜንና ፡ መከራዬን ፡ እይ ÷
ኃጢአቴንም ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡ በለኝ ።
፲፱፤ ጠላቶቼ ፡ እንደ ፡ በዙ ፡ እይ ÷
የግፍም ፡ ጥል ፡ ጠልተውኛል ።
፳፤ ነፍሴን ፡ ጠብቅና ፡ አድነኝ ፤
አንተን ፡ ታምኛለሁና ፡ አልፈር ።
፳፩፤ አንተን ፡ ተስፋ ፡ አድርጌአለሁና ፡
የውሃትና ፡ ቅንነት ፡ ይጠብቁኝ ።
፳፪፤ አቤቱ ÷ እስራኤልን ፡ ከመከራው ፡ ሁሉ ፡ አድነው ።

## መዝሙር ፡ ፳፭ ። (፳፮)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ÷ እኔ ፡ በየውሃቴ ፡ ሄጃለሁና ፡ ፍረድልኝ ፤
በእግዚአብሔርም ፡ አምኛለሁና ፡ አልናወጥም ።

፪፤ አቤቱ ÷ ፍተነኝ ፡ መርምረኝም ፤
ኵላሊቴንና ፡ ልቤን ፡ ፍተን ።
፫፤ ምሕረትህ ፡ በዓይኔ ፡ ፊት ፡ ነውና ÷
በእውነትህም ፡ ተመላለስሁ ።
፬፤ በከንቱ ፡ ሸንጎ ፡ አልተቀመጥሁም ÷
ከዓመፀኞችም ፡ ጋር ፡ አልገባሁም ።
፭፤ የክፉዎችን ፡ ማኅበር ፡ ጠላሁ ÷
ከዝንጉዎችም ፡ ጋር ፡ አልቀመጥም ።
፮፤ እጆቼን ፡ በንጽሕና ፡ አጥባለሁ ፤
አቤቱ ÷ መሠዊያህን ፡ እዞራለሁ ÷
፯፤ የምስጋናን ፡ ድምፅ ፡ እሰማ ፡ ዘንድ ÷
ተአምራትህንም ፡ ሁሉ ፡ እነግር ፡ ዘንድ ።
፰፤ አቤቱ ÷ የቤትህን ፡ ስፍራ ፡
የክብርህንም ፡ ማደሪያ ፡ በታ ፡ ወደድሁ ።
፱፤ ከኃጢአተኞች ፡ ጋር ፡ ነፍሴን ÷
ከደም ፡ ሰዎችም ፡ ጋር ፡ ሕይወቴን ፡ አታጥፋ ።
፲፤ በእጃቸው ፡ ተንኰል ፡ አለባቸው ÷
ቀኛቸውም ፡ መማለጃ ፡ ተሞልታለች ።
፲፩፤ እኔ ፡ ግን ፡ በየውሃቴ ፡ ሄጃለሁ ፤
አድነኝ ፡ ማረኝም ።
፲፪፤ እግሮቼ ፡ በቅንነት ፡ ቆመዋልና ፤
አቤቱ ÷ በማኅበር ፡ አመሰግንሃለሁ ።

## መዝሙር ፡ ፳፮ ፡ (፳፯)

ሳይቀባ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ ብርሃኔና ፡ መድኃኒቴ ፡ ነው ፤
የሚያስፈራኝ ፡ ማን ፡ ነው ?
እግዚአብሔር ፡ የሕይወቴ ፡ መታመኛዋ ፡ ነው ፤
የሚያስደነግጠኝ ፡ ማን ፡ ነው ?
፪፤ ክፉዎች ÷ አስጨናቂዎቼ ፡ ጠላቶቼም ÷
ሥጋዬን ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ በቀረቡ ፡ ጊዜ ÷
እነርሱ ፡ ተሰናከሉና ፡ ወደቁ ።
፫፤ ሠራዊትም ፡ ቢሰፈርብኝ ፡ ልቤ ፡ አይፈራም ፤
ሰልፍም ፡ ቢነሣብኝ ፡ በዚህ ፡ እተማመናለሁ ።
፬፤ እግዚአብሔርን ፡ አንዲት ፡ ነገር ፡ ለመንሁት ፡
እርስዋንም ፡ እሻለሁ ፤
በሕይወቴ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ እኖር ፡ ዘንድ ÷
እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘውንም ፡ አይ ፡
ዘንድ ÷
መቅደሱንም ፡ እመለከት ፡ ዘንድ ።
፭፤ በመከራዬ ፡ ቀን ፡ በድንኳኑ ፡ ሰውሮኛልና ÷
በድንኳኑም ፡ መሸሸጊያ ፡ ሸሽጎኛልና ÷
በዓለት ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርጎኛልና ።
፮፤ እነሆ ÷ አሁን ፡ በዙሪያ ፡ በሉ ፡ በጠላቶቼ ፡ ላይ ፡
ራሴን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገ ፤
በድንኳኑም ፡ የእልልታ ፡ መሥዋዕትን ፡ ሠዋሁ ÷
ለእግዚአብሔር ፡ እቀኛለሁ ፡ እዘምርለትማለሁ ።
፯፤ አቤቱ ÷ ወደ ፡ አንተ ፡ የጮኽሁትን ፡ ቃሌን ፡
ስማኝ ፤
ማረኝና ፡ አድምጠኝ ።
፰፤ አንተ ፡ ፊቴን ፡ እሹት ፡ በልህ ፡ ጊዜ ፡—
አቤቱ ÷ ፊትህን ፡ እሻለሁ ፡ ልቤ ፡ አንተን ፡ አለ ።
፱፤ ፊትህን ፡ ከእኔ ፡ አትሰውር ÷
ተቈጥተህ ፡ ከባሪያህ ፡ ፊቀቅ ፡ አትበል ፤
ረዳት ፡ ሁነኝ ÷ አትጣለኝም ÷
የመድኃኒቴም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ አትተወኝ ።
፲፤ አባቴና ፡ እናቴ ፡ ትተውኛልና ÷
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ተቀበለኝ ።
፲፩፤ አቤቱ ÷ መንገድህን ፡ አስተምረኝ ÷
ስለ ፡ ጠላቶቼም ፡ በቀና ፡ መንገድ ፡ ምራኝ ።
፲፪፤ የሐሰት ፡ ምስክሮችና ፡ ዓመፀኞች ፡ ተነሥተ
ውብኛልና ፡
ለጠላቶቼ ፡ ፈቃድ ፡ አትስጠኝ ።
፲፫፤ የእግዚአብሔርን ፡ ቸርነት ፡ በሕያዋን ፡ ምድር ፡
አይ ፡ ዘንድ ፡ አምናለሁ ።
፲፬፤ እግዚአብሔርን ፡ ተስፋ ፡ አድርግ ፤
በርታ ÷ ልብህም ፡ ይጽና ፤
እግዚአብሔርን ፡ ተስፋ ፡ አድርግ ።

## መዝሙር ፡ ፳፯ ፡ (፳፰)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ÷ ወደ ፡ አንተ ፡ እጠራለሁ ፤
ዝም ፡ ብትለኝ ፡ ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ እንደሚወር
ዱት ፡ እንዳልመስል ÷
አንተ ፡ አምላኬ ÷ ዝም ፡ አትበለኝ ።
፪፤ ወደ ፡ መቅደስህ ፡ ማደሪያ ፡ እጄን ፡ በነሣሁ ፡
ጊዜ ÷
ወደ ፡ አንተ ፡ የጮኽሁትን ፡ የልመናዬን ፡
ቃል ፡ ስማ ።
፫፤ ከኃጥአንና ፡ ከክፉ ፡ አድራጊዎች ፡ ጋር ፡ ነፍ
ሴን ፡ አትውሰዳት ፤
ክፋትም ፡ በልባቸው ፡ እያለ ፡ ከባልንጀራቸው ፡
ጋር ፡ ሰላም ፡ ከሚናገሩት ፡ ጋር ፡ አትጣለኝ ።
፬፤ እንደ ፡ ሥራቸው ፡ እንደ ፡ አካሄዳቸውም ፡
ክፋት ፡ ስጣቸው ፤
እንደ ፡ እጃቸውም ፡ ሥራ ፡ ስጣቸው ፤
ፍዳቸውን ፡ ወደ ፡ ራሳቸው ፡ መልስ ።
፭፤ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሥራ ፡
ወደ ፡ እጆቹም ፡ አደራረግ ፡ አላሰቡምና ፡
ያፈርሳቸዋል ፡ እንጂ ፡ አይሠራቸውም ።
፮፤ የልመናዬን ፡ ቃል ፡ ሰምቶኛልና ፡
እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ።
፯፤ እግዚአብሔር ፡ ኃይሌና ፡ ጋሻዬ ፡ ነው ፤
ልቤ ፡ በእርሱ ፡ ታመነ ፡ እኔም ፡ ተረዳሁ ፤
ሥጋዬም ፡ ደስ ፡ ይለዋል ÷
ፈቅጄም ፡ አመሰግነዋለሁ ።
፰፤ እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ፡ ኃይላቸው ፡ ነው ÷
ለቀባውም ፡ የመድኃኒቱ ፡ መታመኛ ፡ ነው ።
፱፤ ሕዝብህን ፡ አድን ÷ ርስትህንም ፡ ባርክ ፤
ጠብቃቸው ÷ ለዘላለሙም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድር
ጋቸው ።

## መዝሙር ፡ ፳፰ ። (፳፱)

ከድንኳን ፡ በመውጣት ፡ ጊዜ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ የአምላክ ፡ ልጆች ፡ ሆይ ÷ ለእግዚአብሔር ፡
አምጡ ÷
ክብርንና ፡ ምስጋናን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አምጡ ።

፪፤ የስሙን ፡ ክብር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አምጡ ÷
በቅድስናው ፡ ስፍራ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስገዱ ።
፫፤ የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ በውኖች ፡ ላይ ÷
የክብር ፡ አምላክ ፡ አንጐደጐደ ÷
እግዚአብሔር ፡ በብዙ ፡ ውኖች ፡ ላይ ።
፬፤ የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ በኃይል ፡ ነው ፤
የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ በታላቅ ፡ ክብር ፡ ነው ።
፭፤ የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ ዝግባን ፡ ይሰብራል ፤
እግዚአብሔር ፡ የሊባኖስን ፡ ዝግባ ፡ ይቀጠቅጣል ።
፮፤ እንደ ፡ ጥጃ ፡ ሊባኖስን ÷
አንድ ፡ ቀንድ ፡ እንዳለው ፡ አውሬ ፡ ልጅ ፡ ስርዮንን ፡ ያዘልላቸዋል ።
፯፤ የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ የእሳቱን ፡ ነበልባል ፡ ይቈርጣል ።
፰፤ የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ ምድረ ፡ በዳውን ፡ ያናውጣል ÷
እግዚአብሔር ፡ የቃዴስን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ያናውጣል ።
፱፤ የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ ዋላዎችን ፡ ያጠነክራቸዋል ÷
ጫካዎቹንም ፡ ይገልጣል ፤
ሁሉም ፡ በመቅደሱ ፡— ምስጋና ፡ ይላል ።
፲፤ እግዚአብሔር ፡ የጥፋት ፡ ውኃን ፡ ሰብስቦአል ፤
እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ንጉሥ ፡ ሆኖ ፡ ይቀመጣል ።
፲፩፤ እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ፡ ኃይልን ፡ ይሰጣል ፤
እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ በሰላም ፡ ይባርካል ።

## መዝሙር ፡ ፳፱ ። (፴)

ለቤቱ ፡ መመረቅ ፡ ምስጋና ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ÷ ተቀብለኸኛልና ÷
ጠላቶቼንም ፡ ደስ ፡ አላሰኘህብኝምና ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርግሃለሁ ።
፪፤ አቤቱ ፡ አምላኬ ÷ ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኽሁ ፡ ምሕረትም ፡ አደረግህልኝ ።
፫፤ አቤቱ ÷ ነፍሴን ፡ ከሲኦል ፡ አወጣሃት ÷
ወደ ፡ ጕድጓድም ፡ እንዳልወርድ ፡ አዳንኸኝ ።
፬፤ ቅዱሳን ፡ ሆይ ÷ ለእግዚአብሔር ፡ ዘምሩ ÷
ለቅድስናውም ፡ መታሰቢያ ፡ አመስግኑ ።
፭፤ ቍጣው ፡ ለጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ነው ÷
ሞገሱ ፡ ግን ፡ ለሕይወት ፡ ዘመን ፤
ልቅሶ ፡ ማታ ፡ ይመጣል ÷
ጥዋት ፡ ግን ፡ ደስታ ፡ ይሆናል ።
፮፤ እኔም ፡ በደስታዬ ፡— ለዘላለም ፡ አልታወክም ፡ አልሁ ።
፯፤ አቤቱ ÷ በፈቃድህ ፡ ለሕይወቴ ፡ ኃይልን ፡ ሰጠሃት ፤
ፊትህን ፡ መለስህ ÷ እኔም ፡ ደነገጥሁ ።
፰፤ አቤቱ ÷ ወደ ፡ አንተ ፡ ጠራሁ ÷
ወደ ፡ አምላኬም ፡ ለመንሁ ።
፱፤ ወደ ፡ ጥፋት ፡ ብወርድ ፡ በደሜ ፡ ምን ፡ ጥቅም ፡ አለ ?
አፈር ፡ ያመሰግንሃልን ? እውነትህንም ፡ ይናገራልን?
፲፤ እግዚአብሔር ፡ ሰማ ፡ ማረኝም ፤
እግዚአብሔር ፡ ረዳቴ ፡ ሆነኝ ።
፲፩፤ ክብሬ ፡ ትዘምርልህ ፡ ዘንድ ፡ ዝምም ፡ እንዳትል ፡
ልቅሶዬን ፡ ለደስታ ፡ ለወጥህልኝ ÷
ማቄን ፡ ቀድደህ ፡ ደስታንም ፡ አስታጠቅኸኝ ።
፲፪፤ አቤቱ ፡ አምላኬ ÷ ለዘላለም ፡ አመሰግንሃለሁ ።

## መዝሙር ፡ ፴ ። (፴፩)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በማድነቅ ፡ ጊዜ ፤

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ÷ አንተን ፡ ታመንሁ ፤ ለዘላለም ፡ አልፈር ፤
በጽድቅህም ፡ አድነኝ ።
፪፤ ጆሮህን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አዘንብል ÷ ፈጥነህም ፡ አድነኝ ፤
ታድነኝ ፡ ዘንድ ፡ መታመኛ ፡ አምላክና ፡ የመጠጊያ ፡ ቤት ፡ ሁነኝ ።
፫፤ አምባዬና ፡ መጠጊያዬ ፡ አንተ ፡ ነህና ፡
ስለ ፡ ስምህ ፡ መንገዴን ፡ አቅና ፡ ምራኝም ።
፬፤ አንተ ፡ መታመኛዬ ፡ ነህና ፡
ከደበቁብኝ ፡ ወጥመድ ፡ አውጣኝ ።
፭፤ በእጅህ ፡ ነፍሴን ፡ እሰጣለሁ ፤
የእውነት ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ÷ ተቤዥተኸኛል ።
፮፤ ከንቱ ፡ ምናምንቴነትን ፡ የጠበቁትን ፡ ጠላህ ፤
እኔ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታመንሁ ።
፯፤ መከራዬን ፡ አይተሃልና ÷
ነፍሴንም ፡ ከጭንቀት ፡ አድነሃታልና ፡
በምሕረትህ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ሐሤትም ፡ አደርጋለሁ ።
፰፤ በጠላቴ ፡ እጅ ፡ አልዘጋኸኝም ÷
በሰፊም ፡ ስፍራ ፡ እግሮቼን ፡ አቆምህ ።
፱፤ ተቸግሬአለሁና ፡ አቤቱ ፡ ምራኝ ፤
ዓይኔም ፡ ከኀዘን ፡ የተነሣ ፡ ተፈጀች ÷
ነፍሴም ፡ ሆዴም ።
፲፤ ሕይወቴ ፡ በኀዘን ፡ አልቃለችና ÷
ዓመታቴም ፡ በልቅሶ ፡ ጨኸት ፤
ኃይሌ ፡ በችግር ፡ ደከመ ÷
አጥንቶቼም ፡ ተነዋወጡ ።
፲፩፤ በጠላቶቼ ፡ ዘንድ ፡ ተነወርሁ ÷
ይልቁንም ፡ በጎረቤቶቼ ፡ ዘንድ ÷
ለሚያውቁኝም ፡ ፍርሃት ፡ ሆንሁ ፤
በሜዳ ፤ ያዩኝም ፡ ከእኔ ፡ ሸሹ ።
፲፪፤ እንደ ፡ ሞተ ፡ ሰው ፡ ከልብ ፡ ተረሳሁ ÷
እንደ ፡ ተበላሸ ፡ ዕቃም ፡ ሆንሁ ።
፲፫፤ የብዙ ፡ ሰዎችን ፡ ስድብ ፡ ሰምቻለሁና ፤
በዙሪያው ፡ ፍርሃት ፡ ነበረ ፤
በላዬ ፡ በአንድነት ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡
ነፍሴን ፡ ለመንጠቅ ፡ ተማከሩ ።
፲፬፤ አቤቱ ÷ እኔ ፡ ግን ፡ በአንተ ፡ ታመንሁ ፤
አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነህ ፡ አልሁ ።
፲፭፤ ርስቴ ፡ በእጅህ ፡ ነው ፤
ከጠላቶቼ ፡ እጅና ፡ ከሚያሳድዱኝ ፡ አድነኝ ።
፲፮፤ ፊትህን ፡ በባሪያህ ፡ ላይ ፡ አብራ ÷
ስለ ፡ ምሕረትህም ፡ አድነኝ ።

፲፯፡ አቤቱ ÷ አንተን ፡ ጠርቻለሁና ፡ አልፈር ፤
ክፉዎች ፡ ይፈሩ ፡
በሲኦልም ፡ ዝም ፡ ይበሉ ።
፲፰፡ በድፍረትና ፡ በትዕቢት ፡ በመናቅም ፡
በጻድቅ ፡ ላይ ፡ የሚናገሩ ፡
የሽንገላ ፡ ከንፈሮች ፡ ድዳ ፡ ይሁኑ ።
፲፱፡ በአንተ ፡ ለሚያምኑ ፡ በሰው ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ያዘጋጀሃት ፡
ለሚፈሩህም ፡ የሰወርሃት ÷
ቸርነትህ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ በዛች !
፳፡ በፊትህ ፡ መጋረጃ ፡ ከሰው ፡ ክርክር ፡ ትጋርዳቸዋለህ ÷
በድንኳንህም ፡ ከአንደበት ፡ ክርክር ፡ ትሸፍናቸዋለህ ።
፳፩፡ በተከበበ ፡ ከተማ ፡ የሚያስደንቅ ፡ ምሕረቱን ፡ በእኔ ፡ የገለጠ ፡
እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ።
፳፪፡ እኔስ ፡ ከዓይንህ ፡ ፊት ፡ ተጣልሁ ÷
በድንጋጤ ፡ አልሁ ፤
አንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ በጮኽሁ ፡ ጊዜ ፡
የልመናዬን ፡ ቃል ፡ ሰማኸኝ ።
፳፫፡ ሁላችሁ ፡ ቅዱሳኑ ÷ እግዚአብሔርን ፡ ውደዱት ፤
እግዚአብሔር ፡ እውነተኞችን ፡ ይፈልጋል ÷
ትዕቢተኞችንም ፡ ፈጽሞ ፡ ይበቀላቸዋል ።
፳፬፡ በእግዚአብሔር ፡ የምታምኑ ፡ ሁላችሁ ÷
በርቱ ፡ ልባችሁም ፡ ይጽና ።

## መዝሙር ፡ ፴፩ ። (፴፪)

የዳዊት ፡ ትምህርት ።

፩፡ መተላለፉ ፡ የቀረችለት ፡
ኃጢአቱም ፡ የተከደነችለት ፡ ምስጉን ፡ ነው ።
፪፡ እግዚአብሔር ፡ በደልን ፡ የማይቈጥርበት ፡
በመንፈሱም ፡ ሽንገላ ፡ የሌለበት ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ።
፫፡ ሁልጊዜ ፡ ከመጮኼ ፡ የተነሣ ፡
ዝም ፡ በልሁ ፡ ጊዜ ፡ አጥንቶቼ ፡ ተበላሹ ፤
፬፡ በቀንና ፡ በሌሊት ፡ እጅህ ፡ ከብዳብኛለችና ÷
እርጥበቴም ፡ ለበጋ ፡ ትኵሳት ፡ ተለወጠ ።
፭፡ ኃጢአቴን ፡ ለአንተ ፡ አስታወቅሁ ÷
በደሌንም ፡ አልሸፈንሁም ፤
ለእግዚአብሔር ፡ መተላለፌን ፡ እነግራለሁ ፡ አልሁ ፤
አንተም ፡ የልቤን ፡ ኃጢአት ፡ ተውህልኝ ።
፮፡ ስለዚህ ፡ ቅዱስ ፡ ሁሉ ፡ በምቹ ፡ ጊዜ ፡
ወደ ፡ አንተ ፡ ይለምናል ፤
ብዙ ፡ የጥፋት ፡ ውኃም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አይቀርብም ።
፯፡ አንተ ፡ ለእኔ ፡ መሸሸጊያዬ ፡ ነህ ÷
ከጣርም ፡ ትጠብቀኛለህ ፤
ከከበቡኝ ፡ ታድነኝ ፡ ዘንድ ፡ ደስታዬ ፡ ነህ ።
፰፡ አስተምርሃለሁ ፡ በምትሄድበትም ፡ መንገድ ፡ እመራሃለሁ ፤
ዓይኖቼን ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ አጠናለሁ ።
፱፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እንዳይቀርቡ ፡
በልባብና ፡ በልጓም ፡ ጉንጫቸውን ፡ እንደሚለጉሙአቸው ÷
ልብ ፡ እንደሌላቸው ፡
እንደ ፡ ፈረስና ፡ እንደ ፡ በቅሎ ፡ አትሁኑ ።
፲፡ በኃጢአተኛ ፡ ብዙ ፡ መቅሠፍት ፡ አለበት ፤
በእግዚአብሔር ፡ የሚታመነውን ፡ ግን ፡ ምሕረት ፡ ይከብበዋል ።
፲፩፡ ጻድቃን ፡ ሆይ ÷ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ሐሤትም ፡ አድርጉ ፤
ልባችሁም ፡ የቀና ፡ ሁላችሁ ÷ እልል ፡ በሉ ።

## መዝሙር ፡ ፴፪ ። (፴፫)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፡ ጻድቃን ፡ ሆይ ÷ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፤
ለቅኖች ፡ ምስጋና ፡ ይገባል ።
፪፡ እግዚአብሔርን ፡ በመሰንቆ ፡ አመስግኑት ÷
አሥር ፡ አውታርም ፡ ባለው ፡ በበገና ፡ ዘምሩለት ።
፫፡ አዲስ ፡ ቅኔም ፡ ተቀኙለት ÷
በእልልታም ፡ መልካም ፡ ዝማሬ ፡ ዘምሩ ፤
፬፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ቅን ፡ ነውና ፡
ሥራውም ፡ ሁሉ ፡ በእምነት ፡ ነውና ።
፭፡ ጽድቅንና ፡ ፍርድን ፡ ይወድዳል ፤
የእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ምድርን ፡ ሞላች ።
፮፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ሰማዮች ፡ ጸኑ ÷
ሠራዊታቸውም ፡ ሁሉ ፡ በአፉ ፡ እስትንፋስ ፤
፯፡ የባሕርን ፡ ውኃ ፡ እንደ ፡ ረዋት ፡ የሚሰበስበው ÷
ቀላዮችንም ፡ በመዝገቦች ፡ የሚያኖራቸው ።
፰፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትፍራው ÷
በዓለም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉም ፡ ከእርሱ ፡ የተነሣ ፡ ይደንግጡ ።
፱፡ እርሱ ፡ ተናግሮአልና ÷ ሆኑም ፤
እርሱ ፡ አዘዘ ÷ ጸኑም ።
፲፡ እግዚአብሔር ፡ የአሕዛብን ፡ ምክር ፡ ያጠፋል ÷
የአሕዛብንም ፡ አሳብ ፡ ይመልሳል ።
፲፩፡ የእግዚአብሔር ፡ ምክር ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ÷
የልቡም ፡ አሳብ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
፲፪፡ እግዚአብሔር ፡ አምላኩ ፡ የሚሆንለት ፡ ሕዝብ ፡ ምስጉን ፡ ነው ÷
እርሱ ፡ ለርስቱ ፡ የመረጠው ፡ ሕዝብ ።
፲፫፡ እግዚአብሔር ፡ ከሰማይ ፡ ተመለከተ ÷
የሰውንም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ አየ ።
፲፬፡ ከማደሪያው ፡ ቦታ ፡ ሆኖ ፡
በምድር ፡ ወደሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ተመለከተ ÷
፲፭፡ እርሱ ፡ ብቻውን ፡ ልባቸውን ፡ የሠራ ፡
ሥራቸውንም ፡ ሁሉ ፡ የሚያስተውል ።
፲፮፡ ንጉሥ ፡ በሠራዊቱ ፡ ብዛት ፡ አይድንም ÷
ኃያልም ፡ በኃይሉ ፡ ብዛት ፡ አያመልጥም ።
፲፯፡ ፈረስም ፡ ከንቱ ፡ ነው ÷ አያድንም ፤
በኃይሉም ፡ ብዛት ፡ አያመልጥም ።
፲፰፡ እነሆ ÷ የእግዚአብሔር ፡ ዓይኖች ፡ ወደሚፈሩት ፡ ናቸው ÷
በምሕረቱም ፡ ወደሚታመኑ ÷

፲፱፤ ነፍሳቸውን ፡ ከሞት ፡ ያድን ፡ ዘንድ ÷
በራብም ፡ ጊዜ ፡ ይመግባቸው ፡ ዘንድ ።
፳፤ ነፍሳችን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተስፋ ፡ ታደር ገዋለች ÷
ረዳታችንና ፡ መጠጊያችን ፡ እርሱ ፡ ነውና ።
፳፩፤ ልባችን ፡ በእርሱ ፡ ደስ ፡ ይለዋልና ÷
በቅዱስ ፡ ስሙም ፡ ታምነናልና ።
፳፪፤ አቤቱ ÷ ምሕረትህ ፡ በላያችን ፡ ትሁን ÷
በአንተ ፡ እንደ ፡ ታመንን ።

## መዝሙር ፡ ፴፫ ፡ (፴፬)

ባሳደደው ፡ በአቤሜሌክ ፡ ፊት ፡ መልኩን ፡ በለወጠ ፡ ጊዜ ፡ በሄደም ፡ ጊዜ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ እግዚአብሔርን ፡ ሁልጊዜ ፡ እባርከዋለሁ ÷
ምስጋናውም ፡ ዘወትር ፡ በአፌ ፡ ነው ።
፪፤ ነፍሴ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ትከብራለች ÷
ገሮችም ፡ ሰምተው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፫፤ እግዚአብሔርን ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ታላቅ ፡ አድ ርጉት ÷
በአንድነትም ፡ ስሙን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እናድርግ ።
፬፤ እግዚአብሔርን ፡ ፈለግሁት ፡ መለሰልኝም ÷
ከመከራዬም ፡ ሁሉ ፡ አዳነኝ ።
፭፤ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቅረቡ ፡ ያበራላችሁማል ÷
ፊታችሁም ፡ አያፍርም ።
፮፤ ይህ ፡ ችግረኛ ፡ ጮኸ ÷ እግዚአብሔርም ፡ ሰማው ÷
ከመከራውም ፡ ሁሉ ፡ አዳነው ።
፯፤ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ በሚፈሩት ፡ ሰዎች ፡ ዙሪያ ፡ ይሰፍራል ÷ ያድናቸውማል ።
፰፤ እግዚአብሔር ፡ ቸር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ቅመሱ ፡ እዩም ፤
በእርሱ ፡ የሚታመን ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ።
፱፤ የሚፈሩት ፡ አንዳችን ፡ አያጡምና ፡
ቅዱሳኑ ፡ ሁሉ ÷ እግዚአብሔርን ፡ ፍሩት ።
፲፤ ባለጠጎች ፡ ደኸዩ ፡ ተራቡም ÷
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈልጉት ፡ ግን ፡ ከመል ካም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አይጐድሉም ።
፲፩፤ ልጆቼ ፡ ኑ ÷ ስሙኝ ፤
እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ አስተምራችኋለሁ ።
፲፪፤ ሕይወትን ፡ የሚፈቅድ ፡ ሰው ፡ ማን ፡ ነው ?
በጎንም ፡ ዘመን ፡ ለማየት ፡ የሚወድድ ?
፲፫፤ አንደበትህን ፡ ከክፉ ፡ ከልክል ÷
ከንፈሮችህም ፡ ሽንገላን ፡ እንዳይናገሩ ።
፲፬፤ ከክፉ ፡ ሽሽ ፡ መልካምንም ፡ አድርግ ፤
ሰላምን ፡ እሻ ፡ ተከተላትም ።
፲፭፤ የእግዚአብሔር ፡ ዓይኖች ፡ ወደ ፡ ጻድቃን ፡
ጆሮቹም ፡ ወደ ፡ ጩኸታቸው ፡ ናቸውና ።
፲፮፤ መታሰቢያቸውን ፡ ከምድር ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉን ፡ በሚያደርጉ ፡ ላይ ፡ ነው ።
፲፯፤ ጻድቃን ፡ ጮኹ ÷ እግዚአብሔርም ፡ ሰማቸው ፡
ከመከራቸውም ፡ ሁሉ ፡ አዳናቸው ።
፲፰፤ እግዚአብሔር ፡ ልባቸው ፡ ለተሰበረ ፡ ቅርብ ፡ ነው ÷
መንፈሳቸው ፡ የተሰበረውንም ፡ ያድናቸዋል ።
፲፱፤ የጻድቃን ፡ መከራቸው ፡ ብዙ ፡ ነው ÷
እግዚአብሔርም ፡ ከሁሉ ፡ ያድናቸዋል ።
፳፤ እግዚአብሔር ፡ አጥንቶቻቸውን ፡ ሁሉ ፡ ይጠ ብቃል ÷
ከእነርሱም ፡ አንድ ፡ አይሰበርም ።
፳፩፤ ኃጢአተኞችን ፡ ክፉት ፡ ይገድላቸዋል ፡
ጻድቃንንም ፡ የሚጠሉ ፡ ይጸጸታሉ ።
፳፪፤ የባሪያዎቹን ፡ ነፍስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቤዣል ÷
በእርሱም ፡ የሚያምኑ ፡ ሁሉ ፡ አይጸጸቱም ።

## መዝሙር ፡ ፴፬ ። (፴፭)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ÷ የሚበድሉኝን ፡ በድላቸው ÷
የሚዋጉኝንም ፡ ተዋጋቸው ።
፪፤ ጥሩርና ፡ ጋሻ ፡ ያዝ ÷
እኔንም ፡ ለመርዳት ፡ ተነሥ ።
፫፤ ሰይፍህን ፡ ምዘዝ ፡
የሚያሳድዱኝንም ፡ መንገዳቸውን ፡ ዝጋ ፤
ነፍሴን ፡— መድኃኒትሽ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ በላት ።
፬፤ ነፍሴን ፡ የሚሹ ፡ ሁሉ ፡ ይፈሩ ፡ ይጐስቍሉም ፤
ክፉትን ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ የሚያስቡ ፡ ይፈሩ ፡
ወደ ፡ ኋላቸውም ፡ ይበሉ ።
፭፤ በነፋስ ፡ ፊት ፡ እንዳለ ፡ ትቢያ ፡ ይሁኑ ÷
የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ያስጨንቃቸው ።
፮፤ መንገዳቸው ፡ ዳጥና ፡ ጨለማ ፡ ይሁን ÷
የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ያሳድዳቸው ።
፯፤ በከንቱ ፡ ያጠፉኝ ፡ ዘንድ ፡ ወጥመዳቸውን ፡ ሸሽ ገውብኛልና ÷
ነፍሴን ፡ በከንቱ ፡ አበሳጭተዋልና ።
፰፤ ያላወቁት ፡ ወጥመድ ፡ ይምጣባቸው ÷
የሸሸጉትም ፡ ወጥመድ ፡ ይያዛቸው ፤
በዚህ ፡ ወጥመድ ፡ ውስጥ ፡ ይውደቁ ።
፱፤ ነፍሴ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይላታል ÷
በማዳኑም ፡ ሐሤት ፡ ታደርጋለች ።
፲፤ አጥንቶቼ ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ይሉሃል ፡— አቤቱ ÷ እንደ ፡ አንተ ፡ ማን ፡ ነው ?
ችግረኛን ፡ ከሚቀማው ፡ እጅ ÷
ችግረኛንና ፡ ድሀውንም ፡ ከሚነጥቀው ፡ እጅ ፡ ታድነዋለህ ።
፲፩፤ የክፉት ፡ ምስክሮች ፡ ተነሡብኝ ÷
የማላውቀውንም ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ተናገሩ ።
፲፪፤ ስለ ፡ በጎ ፡ ክፉትን ፡ መለሱልኝ ÷
ነፍሴንም ፡ ልጆችን ፡ አሳጡአት ።
፲፫፤ እኔስ ፡ እነርሱ ፡ በታመሙ ፡ ጊዜ ፡ ማቅ ፡ ለበስሁ ÷
ነፍሴንም ፡ በጾም ፡ አደከምኋት ፤
ጸሎቴም ፡ ወደ ፡ ብብቴ ፡ ተመለሰ ።
፲፬፤ ለወዳጄና ፡ ለወንድሜ ፡ እንደማደርግ ፡ አደረ ግሁ ፤
ለእናቱም ፡ እንደሚያለቅስ ፡ ራሴን ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አደረግሁ ።
፲፭፤ በእኔ ፡ ላይ ፡ ተሰበሰቡ ፡ ደስም ፡ አላቸው ፤
ግፈኞች ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ተሰበሰቡ ፡ እኔም ፡ አላ ወቅሁም ፤
ቀደዱኝ ፡ አልተዉኝምም ።

፲፮ ፈተኑኝ ፡ በሣቅም ፡ ዘበቱብኝ ÷
ጥርሳቸውንም ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ አንቀጫቀጩ ።
፲፯ አቤቱ ÷ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ታይልኛለህ ?
ነፍሴን ፡ ከክፉ ፡ ሥራቸው ፡
ብቸኝነቴንም ፡ ከአንበሶች ፡ አድናት ።
፲፰ አቤቱ ÷ በታላቁ ፡ ጉባኤ ፡ ውስጥ ፡ እገዛልሃለሁ ÷
በብዙ ፡ ሕዝብ ፡ መካከልም ፡ አመሰግንሃለሁ ።
፲፱ በግፍ ፡ የሚጠሉኝ ፡ በላዬ ፡ ደስ ፡ አይበላቸው ÷
በከንቱ ፡ የሚጣሉኝም ፡ በዓይናቸው ፡ አይጣቀሱብኝ ።
፳ ለእኔስ ፡ ሰላምን ፡ ይናገሩኛልና ÷
በቍጣም ፡ ሽንገላን ፡ ይመክራሉ ።
፳፩ አፋቸውንም ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ አላቀቁ ፤
እሰይ ፡ እሰይ ÷ ዓይናችን ፡ አየው ፡ ይላሉ ።
፳፪ አቤቱ ÷ አንተ ፡ አየኸው ፤ ዝም ፡ አትበል ፤
አቤቱ ÷ ከእኔ ፡ አትራቅ ።
፳፫ አምላኬ ፡ ጌታዬም ÷ ወደ ፡ ፍርዴ ፡ ተነሥ ÷
አቤቱ ÷ ፍርዴን ፡ አድምጥ ።
፳፬ አቤቱ ፡ አምላኬ ÷ እንደ ፡ ጽድቅህ ፡ ፍረድልኝ ÷
በላዬም ፡ ደስ ፡ አይበላቸው ።
፳፭ በልባቸው ፡— እሰይ ፡ እሰይ ÷ ነፍሳችንን ፡ ደስ ፡ አላት ፡ አይበሉ ፤
ደግሞም ፡— ዋጥነው ፡ አይበሉ ።
፳፮ በመከራዬ ፡ ደስ ፡ የሚላቸው ፡ ይፈሩ ÷
በአንድነትም ፡ ይጐስቍሉ ፤
በእኔ ፡ ላይ ፡ የሚታበዩ ፡ እፍረትንና ፡ ጐስቍልናን ፡ ይልበሱ ።
፳፯ ጽድቄን ፡ የሚወድዱአት ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡
ሐሤትንም ፡ ያድርጉ ፤
የባሪያውን ፡ ሰላም ፡ የሚወድድ ፡ እግዚአብሔር ፡
ታላቅ ፡ ይሁን ፡ ዘወትር ፡ ይበሉ ።
፳፰ ምላሴ ፡ ጽድቅህን ፡
ሁልጊዜም ፡ ምስጋናህን ፡ ይናገራል ።

## መዝሙር ፡ ፴፭ ። (፴፮)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ ኃጢአተኛ ፡ በራሱ ፡ የሚያስት ፡ ነገርን ፡ ይናገራል ÷
የእግዚአብሔርም ፡ ፍርሃት ፡ በዓይኖቹ ፡ ፊት ፡ የለም ።
፪ በአንደበቱ ፡ ሸንግሎአልና ፤
ኃጢአቱ ፡ በገኘችው ፡ ጊዜ ፡ ይጠላታል ።
፫ የአፉ ፡ ቃል ፡ ግፍና ፡ ሽንገላ ፡ ነው ፤
ማስተዋልን ፡ በጎ ፡ ማድረግንም ፡ ተወ ።
፬ በመኝታው ፡ ጠማማነትን ፡ አሰበ ፤
መልካም ፡ በልሆነች ፡ መንገድ ፡ ቆሞአል ፤
ክፋትን ፡ አይንቃትም ።
፭ አቤቱ ÷ ምሕረትህ ፡ በሰማይ ፡ ነው ÷
እውነትህም ፡ ወደ ፡ ደመናት ፡ ትደርሳለች ።
፮ ጽድቅህም ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተራሮች ÷
ፍርድህም ፡ እጅግ ፡ ጥልቅ ፡ ናት ፤
አቤቱ ÷ ሰውንና ፡ እንስሳን ፡ ታድናለህ ።
፯ አቤቱ ÷ ምሕረትህን ፡ እንዴት ፡ አበዛህ !
የሰው ፡ ልጆች ፡ በክንፎችህ ፡ ጥላ ፡ ይታመናሉ ።
፰ ከቤትህ ፡ ጠል ፡ ይጠጣሉ ÷
ከተድላህም ፡ ፈሳሽ ፡ ታጠጣቸዋለህ ።
፱ የሕይወት ፡ ምንጭ ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ ነውና ፤
በብርሃንህ ፡ ብርሃንን ፡ እናያለን ።
፲ ምሕረትህን ፡ በሚያውቁህ ፡ ላይ ÷
ጽድቅህንም ፡ ልባቸው ፡ በቀና ፡ ላይ ፡ ዘርጋ ።
፲፩ የትዕቢት ፡ እግር ፡ አይምጣብኝ ÷
የኃጢአተኞችም ፡ እጅ ፡ አያውከኝ ።
፲፪ ዓመፃን ፡ የሚያደርጉ ፡ ሁሉ ፡ ከዚያ ፡ ወደቁ ፤
ወድቀዋል ÷ መቆምም ፡ አይችሉም ።

## መዝሙር ፡ ፴፮ ። (፴፯)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ በክፉዎች ፡ ላይ ፡ አትቅና ÷
ዓመፃንም ፡ በሚያደርጉ ፡ ላይ ፡ አትቅና ፤
፪ እንደ ፡ ሣር ፡ ፈጥነው ፡ ይደርቃሉና ÷
እንደ ፡ ለመለመ ፡ ቅጠልም ፡ ይረግፋሉና ።
፫ በእግዚአብሔር ፡ ታመን ÷ መልካምንም ፡ አድርግ ÷
በምድርም ፡ ተቀመጥ ÷ ታምነህም ፡ ተሰማራ ።
፬ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይበልህ ÷
የልብህንም ፡ መሻት ፡ ይሰጥሃል ።
፭ መንገድህን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አደራ ፡ ስጥ ÷
በእርሱም ፡ ታመን ÷ እርሱም ፡ ያደርግልሃል ።
፮ ጽድቅህን ፡ እንደ ፡ ብርሃን ፡
ፍርድህንም ፡ እንደ ፡ ቀትር ፡ ያመጣል ።
፯ ለእግዚአብሔር ፡ ተገዛ ፡ ተስፋም ፡ አድርገው ።
መንገድም ፡ በቀናችለትና ፡ ጥመትን ፡ በሚያደርግ ፡ ሰው ፡ አትቅና ።
፰ ከቍጣ ፡ ራቅ ፡ መዓትንም ፡ ተው ፤
እንዳትበድል ፡ አትቅና ።
፱ ክፉ ፡ አድራጊዎች ፡ ይጠፋሉና ፤
እግዚአብሔርን ፡ ተስፋ ፡ የሚያደርጉ ፡ ግን ፡ እነርሱ ፡ ምድርን ፡ ይወርሳሉ ።
፲ ገና ፡ ጥቂት ÷ ኃጢአተኛም ፡ አይኖርም ፤
ትፈልገዋለህ ፡ በታውንም ፡ አታገኝም ።
፲፩ ገሮች ፡ ግን ፡ ምድርን ፡ ይወርሳሉ ÷
በብዙም ፡ ሰላም ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፲፪ ኃጢአተኛ ፡ ጻድቁን ፡ ይመለከተዋል ÷
ጥርሱንም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ያንገጫግጫል ።
፲፫ እግዚአብሔር ፡ ይሥቅበታል ÷
ቀኑ ፡ እንደሚደርስ ፡ አይቶአልና ።
፲፬ ኃጢአተኞች ፡ ሰይፋቸውን ፡ መዘዙ ÷
ቀስታቸውንም ፡ ገተሩ ፡
ድሀውንና ፡ ችግረኛውን ፡ ይጥሉ ፡ ዘንድ ÷
ልበ ፡ ቅኖችንም ፡ ይወጉ ፡ ዘንድ ፤
፲፭ ሰይፋቸው ፡ ወደ ፡ ልባቸው ፡ ይግባ ÷
ቀስታቸውም ፡ ይሰበር ።
፲፮ ለጻድቅ ፡ ያለው ፡ ጥቂት ፡
ከብዙ ፡ ከኃጢአተኞች ፡ ሀብት ፡ ይበልጣል ።
፲፯ የኃጥአን ፡ ክንድ ፡ ትሰበራለችና ፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ጻድቃንን ፡ ይደግፋቸዋል ።

፲፰፤ የንጹሓንን ፡ መንገድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያውቃል ፤
ርስታቸውም ፡ ለዘላለም ፡ ነው ፤
፲፱፤ በክፉ ፡ ዘመንም ፡ አያፍሩም ፤
በራብ ፡ ዘመንም ፡ ይጠግባሉ ።
፳፤ ኀጥኣን ፡ ግን ፡ ይጠፋሉ ፤
የእግዚአብሔር ፡ ጠላቶች ፡ በከበሩና ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ባሉ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ጢስ ፡ ይጠፋሉ ።
፳፩፤ ኃጢአተኛ ፡ ይበደራል ፡ አይከፍልምም ፤
ጻድቅ ፡ ግን ፡ ይራራል ፡ ይሰጣልም ።
፳፪፤ እርሱን ፡ የሚባርኩት ፡ ምድርን ፡ ይወርሳሉና ፤
የሚረግሙት ፡ ግን ፡ ይጠፋሉ ።
፳፫፤ የሰው ፡ አካሄድ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ይጸናል ፤
መንገዱንም ፡ ይወድዳል ።
፳፬፤ ቢወድቅም ፡ ለድንጋፄ አይጣልም ፤
እግዚአብሔር ፡ እጁን ፡ ይዞ ፡ ይደግፈዋልና ።
፳፭፤ ጐለመስሁ ፡ አረጀሁም ፤
ጻድቅ ፡ ሲጣል ፤ ዘሩም ፡ እህል ፡ ሲለምን ፡ አላየሁም ።
፳፮፤ ሁልጊዜ ፡ ይራራል ፡ ያበድርማል ፤
ዘሩም ፡ በበረከት ፡ ይኖራል ።
፳፯፤ ከክፉ ፡ ሽሽ ፤ መልካምንም ፡ አድርግ ፡
ለዘላለምም ፡ ትኖራለህ ።
፳፰፤ እግዚአብሔር ፡ ፍርድን ፡ ይወድዳልና ፤
ቅዱሳኑንም ፡ አይጥላቸውምና ፤
ለዘላለምም ፡ ይጠብቃቸዋል ፡
ለንጹሓንም ፡ ይበቀልላቸዋል ፤
የኀጥኣን ፡ ዘር ፡ ግን ፡ ይጠፋል ።
፳፱፤ ጻድቃን ፡ ምድርን ፡ ይወርሳሉ ፤
በእርስዋም ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራሉ ።
፴፤ የጻድቅ ፡ አፍ ፡ ጥበብን ፡ ያስተምራል ፤
አንደበቱም ፡ ፍርድን ፡ ይናገራል ።
፴፩፤ የአምላኩ ፡ ሕግ ፡ በልቡ ፡ ውስጥ ፡ ነው ፤
በእርምጃውም ፡ አይሰናከልም ።
፴፪፤ ኃጢአተኛ ፡ ጻድቁን ፡ ይመለከተዋል ፤
ሊገድለውም ፡ ይወድዳል ።
፴፫፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በእጁ ፡ አይተወውም ፤
በተፋረደውም ፡ ጊዜ ፡ አያሸንፈውም ።
፴፬፤ እግዚአብሔርን ፡ ደጅ ፡ ጥና ፤ መንገዱንም ፡ ጠብቅ ፤
ምድርንም ፡ ትወርስ ፡ ዘንድ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርግሃል ፤
ኃጢአተኞችም ፡ ሲጠፉ ፡ ታያለህ ።
፴፭፤ ኀጥእን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎ ፡
እንደ ፡ ሊባኖስ ፡ ዝግባም ፡ ለምልሞ ፡ አየሁት ።
፴፮፤ ብመለስ ፡ ግን ፡ አጣሁት ፤
ፈለግሁት ፡ በታውንም ፡ አላገኘሁም ።
፴፯፤ ቅንነትን ፡ ጠብቅ ፤ ጽድቅንም ፡ እይ ፤
ለሰላም ፡ ሰው ፡ ቅሬታ ፡ አለውና ።
፴፰፤ በደለኞች ፡ በአንድነት ፡ ይጠፋሉ ፤
የኃጢአተኞች ፡ ቅሬታ ፡ ይጠፋል ።
፴፱፤ የጻድቃን ፡ መድኃኒታቸው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤
በመከራቸውም ፡ ጊዜ ፡ መጠጊያቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።
፵፤ እግዚአብሔር ፡ ይረዳቸዋል ፤ ያድናቸዋልም ፤
ከኃጢአተኞችም ፡ እጅ ፡ ያወጣቸዋል ፤
ያድናቸዋልም ፤ በእርሱ ፡ ታምነዋልና ።

## መዝሙር ፡ ፴፯ ። (፴፰)

ለሰንበት ፡ መታሰቢያ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ፤ በቍጣህ ፡ አትቅሠፈኝ ፤
በመዓትህም ፡ አትገሥጸኝ ።
፪፤ ፍላጻችህ ፡ ወግተውኛልና ፤
እጅህንም ፡ አከብደህብኛልና ።
፫፤ ከቍጣህ ፡ የተነሣ ፡ ለሥጋዬ ፡ ጤና ፡ የለውም ፤
ከኃጢአቴም ፡ የተነሣ ፡ ለአጥንቶቼ ፡ ሰላም ፡ የላቸውም ።
፬፤ ኃጢአቴ ፡ በራሴ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎአልና ፤
እንደ ፡ ከባድ ፡ ሸክምም ፡ በላዬ ፡ ከብዶአልና ።
፭፤ ከስንፍናዬ ፡ የተነሣ ፡ ቍስሌ ፡ ሸተተ ፡ በሰበሰም ፤
፮፤ እጅግ ፡ ጐሰቈልሁ ፡ ተዋረድሁም ፤
ሁልጊዜም ፡ በትካዜ ፡ እመላለሳለሁ ፤
፯፤ ነፍሴ ፡ ስድብን ፡ ተሞልታለችና ፤
ለሥጋዬም ፡ ጤና ፡ የላትምና ።
፰፤ ታመምሁ ፡ እጅግም ፡ ተቸገርሁ ፤
ከልቤ ፡ ውዝዋዜም ፡ የተነሣ ፡ ጮኽሁ ።
፱፤ አቤቱ ፤ ፈቃዴ ፡ ሁሉ ፡ በፊትህ ፡ ነው ፤
ጭንቀቴም ፡ ከአንተ ፡ አይሰወርም ።
፲፤ ልቤ ፡ ደነገጠብኝ ፤ ኃይሌም ፡ ተወኝኝ ፤
የዓይኖቼም ፡ ብርሃን ፡ ፈዘዘ ።
፲፩፤ ወዳጆቼም ፡ ባልንጀሮቼም ፡ ከቍስሌ ፡ ገለል ፡ ብለው ፡ ቆሙ ፤
ዘመዶቼም ፡ ርቀው ፡ ቆሙ ።
፲፪፤ ነፍሴንም ፡ የሚሹአት ፡ በረቱብኝ ፤
መከራዬንም ፡ የሚፈልጉ ፡ ከንቱን ፡ ተናገሩ ፤
ሁልጊዜም ፡ በሽንገላ ፡ ይመክራሉ ።
፲፫፤ እኔ ፡ ግን ፡ እንደማይሰማ ፡ ደንቆሮ ፤
አፉንም ፡ እንደማይከፍት ፡ ዲዳ ፡ ሆንሁ ።
፲፬፤ እንደማይሰማ ፡ ሰው ፡
በአፉም ፡ ተግሣጽ ፡ እንደሌለው ፡ ሰው ፡ ሆንሁ ።
፲፭፤ አቤቱ ፤ በአንተ ፡ ታምኛለሁና ፤
አቤቱ ፡ አምላኬ ፤ አንተ ፡ ትሰማኛለህ ።
፲፮፤ ጠላቶቼ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ደስ ፡ እንዳይላቸው ፡ ብያለሁና ፤
እግሮቼም ፡ ቢሰናከሉ ፡ ራሳቸውን ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋሉ ።
፲፯፤ እኔስ ፡ ወደ ፡ ማንከስ ፡ ቀርቤአለሁና ፤
ቍስሌም ፡ ሁልጊዜ ፡ በፊቴ ፡ ነውና ።
፲፰፤ በደሌን ፡ እናገራለሁና ፤
ስለ ፡ ኃጢአቴም ፡ እተክዛለሁ ።
፲፱፤ ጠላቶቼ ፡ ሕያዋን ፡ ናቸው ፡ ይበረቱብኛማል ፤
በጠማማነትም ፡ የሚጠሉኝ ፡ በዙ ።
፳፤ ጽድቅን ፡ ስለ ፡ ተከተልሁ ፤
በበጎ ፡ ፋንታ ፡ ክፉን የሚመልሱልኝ ፡ ይጠሉኛል ።

፳፩፡ አቤቱ ÷ አንተ ፡ አትጣለኝ ፤
አምላኬ ÷ ከኔ ፡ አትራቅ ።
፳፪፡ አቤቱ ፡ መድኃኒቴ ÷ እኔን ፡ ለመርዳት ፡ ፍጠን ።

መዝሙር ፡ ፴፰ ። (፴፱)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፡ ለኤዶታም ፤
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፡ በአንደበቴ ፡ እንዳልስት ፡ መንገዴን ፡ እጠብቃለሁ ፤
ኃጢአተኛ ፡ በፊቴ ፡ በተቃወመኝ ፡ ጊዜ ፡
በአፌ ፡ ላይ ፡ ጠበቂ ፡ አኖራለሁ ፡ አልሁ ።
፪፡ ከዝምታ ፡ የተነሣ ፡ እንደ ፡ ዲዳ ፡ ሆንሁ ÷
ለበጎ ፡ እንኳ ፡ ዝም ፡ አልሁ ÷
ቍስሌም ፡ ታደሰብኝ ።
፫፡ ልቤም ፡ በውስጤ ፡ ሞቀብኝ ፤
ከማሰቤም ፡ የተነሣ ፡ እሳት ፡ ነደደ ÷
በአንደበቴም ፡ ተናገርሁ ፦
፬፡ አቤቱ ÷ ፍጻሜዬን ፡ አስታውቀኝ ÷
የዘመኔ ፡ ቍጥሮች ፡ ምን ፡ ያህል ፡ እንደ ፡ ሆኑ ÷
እኔ ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ እንደምቀር ፡ አውቅ ፡ ዘንድ ።
፭፡ እነሆ ÷ ዘመኖቼን ፡ አስረጀሃቸው ፤
አካሌም ፡ በፊትህ ፡ እንደ ፡ ኢምንት ፡ ነው ።
ሕያው ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በእውነት ፡ ከንቱ ፡ ብቻ ፡ ነው ።
፮፡ በከንቱ ፡ ይታወካል ፡ እንጂ ፡
በእውነት ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ይመላለሳል ፤
ያከማቻል ፡ የሚሰበስብለትንም ፡ አያውቅም ።
፯፡ አሁንስ ፡ ተስፋዬ ፡ ማን ፡ ነው ? እግዚአብሔር ፡ አይደለምን ?
ትዕግሥቴም ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
፰፡ ከኃጢአቴ ፡ ሁሉ ፡ አድነኝ ÷
ለሰነፎችም ፡ ስድብ ፡ አታድርገኝ ።
፱፡ አንተ ፡ ሠርተኸኛልና ፡
ዝም ፡ አልሁ ፡ አፌንም ፡ አልከፈትሁም ።
፲፡ መቅሠፍትህን ፡ ከእኔ ፡ አርቅ ÷
ከእጅህ ፡ ብርታት ፡ የተነሣ ፡ አልቄአለሁና ።
፲፩፡ በተግሣጽህ ፡ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ ሰውን ፡ ዘለፍኸው ÷
ነፍሱም ፡ እንደ ፡ ሸረሪት ፡ ድር ፡ ታልቃለች ፤
በእውነት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ነው ።
፲፪፡ አቤቱ ÷ ጸሎቴን ፡ ስማ ÷ ጩኸቴንም ፡ አድምጥ ÷
ልቅሶዬንም ፡ ቸል ፡ አትበልኝ ፤
እኔ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ መጻተኛ ፡ ነኝና ÷
እንደ ፡ አባቶቼም ፡ እንግዳ ፡ ነኝና ።
፲፫፡ ወደማልመለስበት ፡ ሳልሄድ ፡ ዐርፍ ፡ ዘንድ ፡ ተወኝ ።

መዝሙር ፡ ፴፱ ። (፵)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፡ ቆይቼ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደጅ ፡ ጠናሁት ÷
እርሱም ፡ ዘንበል ፡ አለልኝ ፡ ጩኸቴንም ፡ ሰማኝ ።
፪፡ ከጥፋት ፡ ጕድጓድ ፡ ከረግረግም ፡ ጭቃ ፡ አወጣኝ ÷
እግሮቼንም ፡ በድንጋይ ፡ ላይ ፡ አቆማቸው ÷
አረማመዴንም ፡ አጸና ።
፫፡ አዲስ ፡ ዝማሬን ፡ ለአምላካችን ፡ ምስጋና ፡ በአፌ ፡ ጨመረ ፤
ብዙዎች ፡ ያያሉ ፡ ይፈሩማል ÷
በእግዚአብሔርም ፡ ይታመናሉ ።
፬፡ እግዚአብሔርን ፡ የታመነ ፡
ወደ ፡ ትዕቢተኛና ፡ ወደ ፡ ሐሰተኛ ፡ ያልተመለከተ ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ።
፭፡ አቤቱ ፡ አምላኬ ÷ ያደረግኸው ፡ ተአምራት ፡ ብዙ ፡ ነው ÷
አሳብህንም ፡ ምንም ፡ የሚመስለው ፡ የለም ፤
በወራም ፡ ብናገርም ፡ ከቍጥር ፡ ሁሉ ፡ በዛ ።
፮፡ መሥዋዕትንና ፡ ቍርባንን ፡ አልወደድህም ፤
ሥጋን ፡ አዘጋጀህልኝ ፤
የሚቃጠለውንና ፡ ስለ ፡ ኃጢአት ፡ የሚቀርበውን ፡ መሥዋዕት ፡ አልሻህም ።
፯፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አልሁ ፦ እነሆ ÷ መጣሁ ፤
ስለ ፡ እኔ ፡ በመጽሐፍ ፡ ራስ ፡ ተጽፎአል ፤
፰፡ አምላኬ ፡ ሆይ ÷ ፈቃድህን ፡ ለማድረግ ፡ ወደድሁ ÷
ሕግህም ፡ በልቤ ፡ ውስጥ ፡ ነው ።
፱፡ በታላቅ ፡ ጉባኤ ፡ ጽድቅን ፡ አወራሁ ፤
እነሆ ÷ ከንፈሮቼን ፡ አልከለክልም ፤
አቤቱ ÷ አንተ ፡ ጽድቄን ፡ታውቃለህ ።
፲፡ እውነትህንም ፡ በልቤ ፡ ውስጥ ፡ አልሰወርሁም ÷
ማዳንህንም ፡ ተናገርሁ ፤
ምሕረትህንና ፡ እውነትህን ፡ ከታላቅ ፡ ጉባኤ ፡ አልሰወርሁም ።
፲፩፡ አቤቱ ÷ አንተ ፡ ምሕረትህን ፡ ከእኔ ፡ አታርቅ ፤
ቸርነትህና ፡ እውነትህ ፡ ዘወትር ፡ ይጠብቁኝ ።
፲፪፡ ቍጥር ፡ የሌላት ፡ ክፋት ፡ አግኝታኛለችና ፤
ኃጢአቶቼ ፡ ያዙኝ ÷ ማየትም ፡ ተሳነኝ ፤
ከራሴ ፡ ጠጕር ፡ ይልቅ ፡ በዙ ÷ ልቤም ፡ ተወኝ ።
፲፫፡ አቤቱ ÷ ታድነኝ ፡ ዘንድ ፡ ፍቀድ ፤
አቤቱ ÷ እኔን ፡ ለመርዳት ፡ ፍጠን ።
፲፬፡ ነፍሴን ፡ ለማጥፋት ፡ የሚወድዱ ፡ ይፈሩ ፥
በአንድነትም ፡ ይጐስቍሉ ፤
በእኔ ፡ ላይ ፡ ክፋትን ፡ ሊያደርጉ ፡ የሚወድዱ ፡
ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ይመለሱ ፡ ይጐስቍሉም ።
፲፭፡ እሰይ ፡ እሰይ ፡ የሚሉኝ ፡
እፍረታቸውን ፡ ወዲያው ፡ ይከፈሉ ።
፲፮፡ አቤቱ ÷ የሚፈልጉህ ፡ ሁሉ ፡
በአንተ ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡ ሐሤትም ፡ ያድርጉ ፤
ሁልጊዜ ፡ ማዳንህን ፡ የሚወድዱ ፡
ዘወትር ፦ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ይሁን ፡ ይበሉ ።
፲፯፡ እኔ ፡ ችግረኛና ፡ ምስኪን ፡ ነኝ ÷
ጌታ ፡ ግን ፡ ያስብልኛል ፤
አንተ ፡ ረዳቴና ፡ መድኃኒቴ ፡ ነህ ፤
አምላኬ ፡ ሆይ ÷ አትዘግይ ።

## መዝሙር ፡ ፵ ። (፵፩)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ ለችግረኛና ፡ ለምስኪን ፡ የሚያስብ ፡ ምስጉን ፡ ነው ፤
እግዚአብሔር ፡ በክፉ ፡ ቀን ፡ ያድነዋል ።
፪፤ እግዚአብሔር ፡ ይጠብቀዋል ፥ ሕያውም ፡ ያደርገዋል ፥
በምድር ፡ ላይም ፡ ያስመሰግነዋል ፥
በጠላቶቹም ፡ እጅ ፡ አያሳልፈውም ።
፫፤ እግዚአብሔር ፡ በደዌው ፡ አልጋ ፡ ሳለ ፡ ይረዳዋል ፤
መኝታውን ፡ ሁሉ ፡ በበሽታው ፡ ጊዜ ፡ ያነጥፍለታል ።
፬፤ እኔስ ፡— አቤቱ ፥ ማረኝ ፤
አንተን ፡ በድያለሁና ፡ ነፍሴን ፡ ፈውሳት ፡ አልሁ ።
፭፤ ጠላቶቼም ፡ በላዬ ፡ ክፋትን ፡ ይናገራሉ ፡—
መቼ ፡ ይሞታል ፡ ስሙስ ፡ መቼ ፡ ይሻራል ? ይላሉ ።
፮፤ እኔን ፡ ለማየት ፡ ቢገባ ፡ ከንቱን ፡ ይናገራል ፤
ልቡ ፡ ኃጢአትን ፡ ሰበሰበለት ፤
ወደ ፡ ሜዳ ፡ ይወጣል ፡ ይናገራልም ።
፯፤ በላዬ ፡ በመተባበር ፡ ጠላቶቼ ፡ ሁሉ ፡ ይሾከሾኩብኛል ፥
በእኔ ፡ ላይም ፡ ክፋትን ፡ ያስባሉ ።
፰፤ ክፉ ፡ ነገር ፡ መጣበት ፤
ተኝቶአል ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አይነሣም ፡ ይላሉ ።
፱፤ ደግሞ ፡ የሰላሜ ፡ ሰው ፡ የታመንሁበት ፡
እንጀራዬን ፡ የበላ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ተረከዙን ፡ አነሣ ።
፲፤ አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፥ ማረኝ ፥
እመልስላቸውም ፡ ዘንድ ፡ አስነሣኝ ።
፲፩፤ ጠላቴ ፡ እልል ፡ አይልብኝምና ፡
ስለዚህ ፡ እንደ ፡ ወደድኸኝ ፡ አወቅሁ ።
፲፪፤ እኔን ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ቅንነቴ ፡ ተቀበልኸኝ ፥
በፊትህም ፡ ለዘላለም ፡ አጸናኸኝ ።
፲፫፤ ከዘላለም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ።
አሜን ፡ አሜን ።

## መዝሙር ፡ ፵፩ ። (፵፪)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የቆሬ ፡ ልጆች ፡ ትምህርት ።

፩፤ ዋላ ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ምንጭ ፡ እንደሚናፍቅ ፥
አቤቱ ፥ እንዲሁ ፡ ነፍሴ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ትናፍቃለች ።
፪፤ ነፍሴ ፡ ወደ ፡ ሕያው ፡ አምላክ ፡ ተጠማች ፤
መቼ ፡ እደርሳለሁ ? የአምላክንስ ፡ ፊት ፡ መቼ ፡ አያለሁ ?
፫፤ ዘወትር ፡— አምላክህ ፡ ወዴት ፡ ነው ? ሲሉኝ ፡
እንባዬ ፡ በቀንና ፡ በሌሊት ፡ ምግብ ፡ ሆነኝ ።
፬፤ ይህን ፡ ሳስብ ፡ ነፍሴ ፡ በእኔ ፡ ውስጥ ፡ ፈሰሰች ፥
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ምስጋና ፡
መኖሪያ ፡ ስፍራ ፡ እገባለሁና ፤
በዓል ፡ የሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ የደስታና ፡ ምስጋና ፡ ቃል ፡ አሰሙ ።
፭፤ ነፍሴ ፡ ሆይ ፥ ለምን ፡ ታዝኛለሽ ? ለምንስ ፡ ታውኪኛለሽ ?
የፊቴን ፡ መድኃኒት ፡ አምላኬን ፡ አመሰግነው ፡ ዘንድ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ታመኚ ።
፮፤ አምላኬ ፡ ሆይ ፥ ነፍሴ ፡ በእኔ ፡ ውስጥ ፡ ታወከች ፤
ስለዚህ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ምድር ፡
በአርሞንኤምም ፡ በታናሹ ፡ ተራራ ፡ አስብሃለሁ ።
፯፤ በፍዋፍዋቴህ ፡ ድምፅ ፡ ቀላይ ፡ ቀላይን ፡ ትጠራታለች ፤
ማዕበልህና ፡ ሞገድህ ፡ ሁሉ ፡ በላዬ ፡ አለፈ ።
፰፤ እግዚአብሔር ፡ በቀን ፡ ቸርነቱን ፡ ያዝዛል ፥
በሌሊትም ፡ ዝማሬው ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ይሆናል ፤
የእኔ ፡ ስእለት ፡ ለሕይወቴ ፡ አምላክ ፡ ነው ።
፱፤ እግዚአብሔርን ፡— አንተ ፡ መጠጊያዬ ፡ ነህ ፤
ለምን ፡ ረሳኸኝ ?
ጠላቶቼ ፡ ሲያስጨንቁኝ ፡ ለምን ፡ አዝኜ ፡ እመላለሳለሁ ? እለዋለሁ ።
፲፤ ጠላቶቼ ፡ ሁልጊዜ ፡— አምላክህ ፡ ወዴት ፡ ነው ? በሉኝ ፡ ጊዜ ፡
አጥንቶቼን ፡ እየቀለጣጠሙ ፡ ሰደቡኝ ።
፲፩፤ ነፍሴ ፡ ሆይ ፥ ለምን ፡ ታዝኛለሽ ? ለምንስ ፡ ታውኪኛለሽ ?
የፊቴን ፡ መድኃኒት ፡ አምላኬን ፡ አመሰግነው ፡ ዘንድ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ታመኚ ።

## መዝሙር ፡ ፵፪ ። (፵፫)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ፥ ፍረድልኝ ፥
ከጽድቅ ፡ ከራቁ ፡ ሕዝብም ፡ ከርክሬን ፡ ተከራከር ፤
ከሽንጋይና ፡ ከግፈኛ ፡ ሰው ፡ አድነኝ ።
፪፤ አንተ ፡ አምላኬ ፡ ኃይሌም ፥ ለምን ፡ ትተወኛለህ ?
ጠላቶቼ ፡ ሲያስጨንቁኝ ፡ ለምን ፡ አዝኜ ፡ እመላለሳለሁ ?
፫፤ ብርሃንህንና ፡ እውነትህን ፡ ላክ ፤
እነርሱ ፡ ይምሩኝ ፥
ወደ ፡ ቅድስናህ ፡ ተራራና ፡ ወደ ፡ ማደሪያህ ፡ ይውሰዱኝ ።
፬፤ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፥
ጕልማስነቴንም ፡ ደስ ፡ ወዳሰኘኝ ፡ ወደ ፡ አምላኬ ፡ እገባለሁ ፤
አቤቱ ፡ አምላኬ ፥ በበገና ፡ አመሰግንሃለሁ ።
፭፤ ነፍሴ ፡ ሆይ ፥ ለምን ፡ ታዝኛለሽ ? ለምንስ ፡ ታውኪኛለሽ ?
የፊቴን ፡ መድኃኒት ፡ አምላኬን ፡ አመሰግነው ፡ ዘንድ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ታመኚ ።

## መዝሙር ፡ ፵፫ ። (፵፬)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የቆሬ ፡ ልጆች ፡ ትምህርት ።

፩ አቤቱ ÷ በጆሮአችን ፡ ሰማን ÷
አባቶቻችንም ፡ በዘመናቸው ፡ በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ የሠራኸውን ፡ ሥራ ፡ ነገሩን ።
፪ እጅህ ፡ አሕዛብን ፡ አጠፋች ÷ እነርሱንም ፡ ተከልህ ፤
አሕዛብን ፡ ሣቀይኸቸው ፡ አሳደድኻቸውም ።
፫ በሰይፋቸው ፡ ምድርን ፡ አልወረሱም ፡
ክንዳቸውም ፡ አላዳናቸውም ፤
ቀኝህና ፡ ክንድህ ፡ የፊትህም ፡ ብርሃን ፡ ነው ፡ እንጂ ፤
ወድደሃቸዋልና ።
፬ አምላኬና ፡ ንጉሤ ፡ አንተ ፡ ነህ ፤
ለያዕቆብ ፡ መድኃኒትን ፡ እዘዝ ።
፭ በአንተ ፡ ጠላቶቻችንን ፡ እንወጋቸዋለን ÷
በስምህም ፡ በላያችን ፡ የቆሙትን ፡ እናዋርዳቸዋለን ።
፮ በቀስቴ ፡ የምታምን ፡ አይደለሁምና ÷
ሰይፌም ፡ አያድነኝምና ፤
፯ አንተ ፡ ግን ፡ ከጠላቶቻችን ፡ አዳንኸን ÷
የሚጠሉንንም ፡ አሳፈርሃቸው ።
፰ ሁልጊዜ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እንከብራለን ÷
ስምህንም ፡ ለዘላለም ፡ እናመሰግናለን ።
፱ አሁን ፡ ግን ፡ ጠላኸን ፡ አሳፈርኸንም ÷
ከሠራዊታችንም ፡ ጋር ፡ አትወጣም ።
፲ ከጠላቶቻችንም ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ኋላችን ፡ መለስኸን ÷
የሚጠሉንም ፡ ተነጣጠቁን ።
፲፩ እንደ ፡ በጎች ፡ ሊበሉን ፡ ሰጠኸን ÷
ወደ ፡ አሕዛብም ፡ በተንኸን ።
፲፪ ሕዝብህን ፡ ያለ ፡ ዋጋ ፡ ሰጠህ ÷
በመለወጣቸውም ፡ ትርፍ ፡ የለም ።
፲፫ ለጎረቤቶቻችን ፡ ስድብ ÷
በዙሪያችንም ፡ ላሉ ፡ መሣቂያና ፡ መዘበቻ ፡ አደረግኸን ።
፲፬ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ምሳሌ ÷
በሕዝብም ፡ ዘንድ ፡ የራስ ፡ መንቀሳቀሻ ፡ አደረግኸን ።
፲፭ ጕስቍልናዬ ፡ ሁልጊዜ ፡ በፊቴ ፡ ነው ÷
የፊቴም ፡ እፍረት ፡ ሸፈነኝ ።
፲፮ ከሚሳደብና ፡ ከሚላገድ ፡ ቃል ፡ የተነሣ ÷
ከጠላትና ፡ ከቂመኛ ፡ ፊት ፡ የተነሣ ፡ ነው ።
፲፯ ይህ ፡ ሁሉ ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ ደረሰ ÷ አልረሳንህም ÷
ኪዳንህንም ፡ አልወነጀልንም ።
፲፰ ልባችን ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ አልተመለሰም ÷
ፍለጋችንም ፡ ከመንገድህ ፡ ፈቀቅ ፡ አላለም ፤
፲፱ በክፉ ፡ ስፍራ ፡ አዋርደኸናልና ÷
በሞት ፡ ጥላም ፡ ሰውረኸናልና ።
፳ የአምላካችንን ፡ ስም ፡ ረስተንስ ፡ ቢሆን ÷
እጃችንንም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ አምላክ ፡ አንሥተንስ ፡ ቢሆን ÷
፳፩ እግዚአብሔር ፡ ይህንን ፡ አይመረምርም ፡ ነበርን ?
እርሱ ፡ ልብ ፡ የሰወረውን ፡ ያውቃልና ።
፳፪ ስለ ፡ አንተ ፡ ሁልጊዜ ፡ ተገድለናል ÷
እንደሚታረዱም ፡ በጎች ፡ ሆነናል ።
፳፫ አቤቱ ÷ ንቃ ፤ ለምንስ ፡ ትተኛለህ ?
ተነሥ ÷ ለዘወትርም ፡ አትጣለን ።
፳፬ ለምንስ ፡ ፊትህን ፡ ትሰውራለህ ?
መከራችንንና ፡ ችግራችንንስ ፡ ለምን ፡ ትረሳለህ ?
፳፭ ነፍሳችን ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ ተጐሳቍላለችና ÷
ሆዳችንም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ተጣብቃለችና ።
፳፮ አቤቱ ÷ ተነሥና ፡ እርዳን ÷
ስለ ፡ ስምህም ፡ ተቤዠን ።

## መዝሙር ፡ ፵፬ ። (፵፭)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በመለከቶች ፤ የቆሬ ፡ ልጆች ፡ ትምህርት ፤ የፍቅር ፡ መዝሙር ።

፩ ልቤ ፡ መልካም ፡ ነገርን ፡ አፈለቀ ÷
እኔ ፡ ሥራዬን ፡ ለንጉሥ ፡ እነግራለሁ ፤
አንደበቴ ፡ እንደ ፡ ፈጣን ፡ ጸሓፊ ፡ ብርዕ ፡ ነው ።
፪ ውበትህ ፡ ከሰው ፡ ልጆች ፡ ይልቅ ፡ ያምራል ፤
ሞገስ ፡ በከንፈሮችህ ፡ ፈሰሰ ፤
ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ባረከህ ።
፫ ኃያል ፡ ሆይ ÷ በቍንጅናህና ፡ በውበትህ ፡
ሰይፍህን ፡ በወገብህ ፡ ታጠቅ ።
፬ ስለ ፡ ቅንነትና ፡ ስለ ፡ የዋህነት ፡ ስለ ፡ ጽድቅም ፡
አቅና ፡ ተከናወን ፡ ንገሥም ፤
ቀኝህም ፡ በክብር ፡ ይመራሃል ።
፭ ኃያል ፡ ሆይ ÷ ፍላጻዎችህ ፡ የተሳሉ ፡ ናቸው ÷
እነርሱም ፡ በንጉሥ ፡ ጠላቶች ፡ ልብ ፡ ውስጥ ፡ ይገባሉ ÷
አሕዛብም ፡ በበታችህ ፡ ይወድቃሉ ።
፮ አምላክ ፡ ሆይ ÷ ዙፋንህ ፡ ለዘላለም ፡ ነው ፤
የመንግሥትህ ፡ በትር ፡ የቅንነት ፡ በትር ፡ ነው ።
፯ ጽድቅን ፡ ወደድህ ፡ ዓመፃንም ፡ ጠላህ ፤
ስለዚህ ፡ ከባልንጀሮችህ ፡ ይልቅ ፡
እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ የደስታ ፡ ዘይትን ፡ ቀባህ ።
፰ በልብሶችህ ፡ ሁሉ ፡ ከርቤና ፡ ሽቱ ፡ ዝባድም ፡ አሉ ፤
ከዝሆን ፡ ጥርሶች ፡ አዳራሽ ፡ ደስ ፡ ያሰኙሃል ።
፱ የንጉሦች ፡ ሴት ፡ ልጆች ፡ ለክብርህ ፡ ናቸው ፤
በወርቅ ፡ ልብስ ፡ ተጐናጽፋና ፡ ተሸፋፍና ፡
ንግሥቲቱ ፡ በቀኝህ ፡ ትቆማለች ።
፲ ልጄ ፡ ሆይ ÷ ስሚ ፡ እዪ ፡ ጆሮሽንም ፡ አዘንብዪ ፤
ወገንሽን ፡ ያባትሽንም ፡ ቤት ፡ እርሺ ፤
፲፩ ንጉሥ ፡ ውበትሽን ፡ ወድዶአልና ÷
እርሱ ፡ ጌታሽ ፡ ነውና ።
፲፪ የጢሮስ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ መንሻን ፡ ይዘው ፡ ይሰግዱለታል ።
የምድር ፡ ባለጠጎች ፡ አሕዛብ ፡ በፊትሽ ፡ ይማለላሉ ።
፲፫ ለሐሴቦን ፡ ንጉሥ ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡ ክብርዋ ፡ ነው ፤
ልብስዋ ፡ የወርቅ ፡ መጐናጸፊያ ፡ ነው ።
፲፬ በኋላዋ ፡ ደናግሉን ፡ ለንጉሥ ፡ ይወስዷሉ ÷

በልንጀሮችዋንም ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ያቀርባሉ ፤
፲፭ በደስታና ፡ በሐሴት ፡ ይወስዱአቸዋል ፤
ወደ ፡ ንጉሥ ፡ እልፍኝም ፡ ያስገቡአቸዋል ።
፲፮ በአባቶችሽ ፡ ፋንታ ፡ ልጆች ፡ ተወለዱልሽ ፤
በምድርም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ገዥዎች ፡ አድርገሽ ፡ ትሾሚያቸዋለሽ ።
፲፯ ልጅ ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡ ስምሽን ፡ ያሳስባሉ ፤
ስለዚህ ፡ ለዓለምና ፡ ለዘላለም ።
አሕዛብ ፡ ይገዙልሃል ።

## መዝሙር ፡ ፵፭ ። (፵፮)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ ስለ ፡ ምሥጢር ፤ የቆሬ ፡ ልጆች ፡ መዝሙር ።

፩ አምላካችን ፡ መጠጊያችንና ፡ ኃይላችን ፤
በገኘን ፡ በታላቅ ፡ መከራም ፡ ረዳታችን ፡ ነው ።
፪ ስለዚህ ፡ ምድር ፡ ብትነዋወጥ ፤
ተራሮችም ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ልብ ፡ ቢወሰዱ ፡ አንፈራም ።
፫ ውኆቻቸው ፡ ጮኹ ፡ ተናወጡም ፤
ተራሮችም ፡ ከኃይሉ ፡ የተነሣ ፡ ተናወጡ ።
፬ የወንዝ ፡ ፈሳሾች ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ከተማ ፡ ደስ ፡ ያሰኛሉ ፤
ልዑል ፡ ማደሪያውን ፡ ቀደሰ ።
፭ እግዚአብሔር ፡ በመካከልዋ ፡ ነው ፡ አትናወጥም ፤
እግዚአብሔርም ፡ ፈጥኖ ፡ ይረዳታል ።
፮ አሕዛብ ፡ ተናወጡ ፡ መንግሥታትም ፡ ተመለሱ ፤
እርሱ ፡ ቃሉን ፡ ሰጠ ፤ ምድርም ፡ ተንቀጠቀጠች ።
፯ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ነው ፤
የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ መጠጊያችን ፡ ነው ።
፰ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፤
በምድር ፡ ያደረገውንም ፡ ተአምራት ፡ እንድታዩ ፡ ኑ ።
፱ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ጦርነትን ፡ ይሽራል ፤
ቀስትን ፡ ይሰብራል ፤ ጦርንም ፡ ይቈርጣል ፤
በእሳትም ፡ ጋሻን ፡ ያቃጥላል ።
፲ ዕረፉ ፤ እኔም ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እወቁ ፤
በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እላለሁ ፤
በምድርም ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እላለሁ ።
፲፩ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ነው ፤
የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ መጠጊያችን ፡ ነው ።

## መዝሙር ፡ ፵፮ ። (፵፯)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የቆሬ ፡ ልጆች ፡ መዝሙር ።

፩ አሕዛብ ፡ ሁላችሁ ፤ እጆቻችሁን ፡ አጨብጭቡ ፤
በደስታ ፡ ቃልም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ በሉ ።
፪ እግዚአብሔር ፡ ልዑል ፡ ግሩምም ፡ ነውና ፤
በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይም ፡ ታላቅ ፡ ንጉሥ ፡ ነውና ።
፫ አሕዛብን ፡ ከእኛ ፡ በታች ፤
ወገኖችንም ፡ ከእግራችን ፡ በታች ፡ አስገዛልን ።
፬ ለርስቱ ፡ እኛን ፡ መረጠን ፤
የወደደውን ፡ የያዕቆብን ፡ ውበት ።
፭ አምላክ ፡ በእልልታ ፤
እግዚአብሔር ፡ በመለከት ፡ ድምፅ ፡ ዐረገ ።
፮ ዘምሩ ፤ ለአምላካችን ፡ ዘምሩ ፤
ዘምሩ ፤ ለንጉሣችን ፡ ዘምሩ ።
፯ እግዚአብሔር ፡ ለምድር ፡ ሁሉ ፡ ንጉሥ ፡ ነውና ፤
በማስተዋል ፡ ዘምሩ ።
፰ እግዚአብሔር ፡ በአሕዛብ ፡ ላይ ፡ ነገሠ ፤
እግዚአብሔር ፡ በቅድስናው ፡ ዙፋን ፡ ይቀመጣል ።
፱ የምድር ፡ ኃይለኞች ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ናቸውና ፤
የአሕዛብ ፡ አለቆች ፡ ወደ ፡ አብርሃም ፡ አምላክ ፡ ተሰበሰቡ ፤
እርሱንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጉት ።

## መዝሙር ፡ ፵፯ ። (፵፰)

በሁለተኛ ፡ ሰንበት ፡ የቆሬ ፡ ልጆች ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩ እግዚአብሔር ፡ ትልቅ ፡ ነው ፤
በአምላካችን ፡ ከተማ ፡ በተቀደሰው ፡ ተራራ ፡ ምስጋናው ፡ ብዙ ፡ ነው ።
፪ በሰሜን ፡ ወገን ፡ በመልካም ፡ ስፍራ ፡ የቆመ ፡
የምድር ፡ ሁሉ ፡ ደስታ ፡ የጽዮን ፡ ተራራ ፡ ነው ፤
እርሱም ፡ የትልቁ ፡ ንጉሥ ፡ ከተማ ፡ ነው ።
፫ እግዚአብሔር ፡ በአዳራሾችዋ ፡ መጠጊያ ፡ ሆኖ ፡ ይታወቃል ።
፬ እነሆ ፤ ነገሥታት ፡ ተከማችተው ፡ በአንድነት ፡ መጥተዋል ።
፭ እነርሱስ ፡ አይተው ፡ ተደነቁ ፤ ደነገጡ ፤ ታወኩ ።
፮ መንቀጥቀጥ ፡ እንደ ፡ ወላድ ፡ ምጥ ፡ በዚያ ፡ ያዛቸው ።
፯ በኃይለኛ ፡ ነፋስ ፡ የተርሴስን ፡ መርከቦች ፡ ትሰብራለህ ።
፰ እንደ ፡ ሰማን ፡ እንዲሁ ፡ አየን ፤
በሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ከተማ ፤ በአምላካችን ፡ ከተማ ፤
እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ያጸናታል ።
፱ አምላክ ፡ ሆይ ፤ በሕዝብህ ፡ መካከል ፡ ምሕረትህን ፡ ተቀበልን ።
፲ አምላክ ፡ ሆይ ፤ እንደ ፡ ስምህ ፡
እንዲሁም ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ምስጋናህ ፡ ነው ፤
ቀኝህ ፡ ጽድቅን ፡ የተሞላች ፡ ናት ።
፲፩ አቤቱ ፤ ስለ ፡ ፍርድህ ፡ የጽዮን ፡ ተራራ ፡ ደስ ፡ ይበለው ፤
የአይሁድም ፡ ሴት ፡ ልጆች ፡ ሐሤት ፡ ያድርጉ ።
፲፪ ጽዮንን ፡ ክበቡአት ፤
በዙሪያዋም ፡ ተመላለሱ ፤
ግንቦችዋንም ፡ ቍጠሩ ፤
፲፫ በብርታትዋ ፡ ልባችሁን ፡ አኑሩ ፤
አዳራሽዋን ፡ አስቡ ፤
ለሚመጣው ፡ ትውልድ ፡ ትነግሩ ፡ ዘንድ ።
፲፬ ለዓለምና ፡ ለዘላለም ፡ ይህ ፡ አምላካችን ፡ ነው ፤
እርሱም ፡ ለዘላለም ፡ ይመራናል ።

## መዝሙር ፡ ፵፰ ። (፵፱)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የቆሬ ፡ ልጆች ፡ መዝሙር ።

፩፤ አሕዛብ ፡ ሁላችሁ ÷ ይህን ፡ ስሙ ፤
በዓለም ፡ የምትኖሩም ፡ ሁላችሁ ÷ አድምጡ ፤
፪፤ ዝቅተኞችና ፡ ከፍተኞች ÷
ባለጠጎችና ፡ ድሆች ፡ በአንድነት ።
፫፤ አፌ ፡ ጥበብን ፡ ይናገራል ÷
የልቤም ፡ አሳብ ፡ ማስተዋልን ።
፬፤ ጆሮዬን ፡ ወደ ፡ ምሳሌ ፡ አዘነብላለሁ ÷
በበገናም ፡ ምሥጢሬን ፡ እገልጣለሁ ።
፭፤ ኃጢአት ፡ ተረከዜን ፡ በከበበኝ ፡ ጊዜ ፡
በክፉ ፡ ቀን ፡ ለምን ፡ እፈራለሁ ?
፮፤ በኃይላቸው ፡ የሚታመኑ ÷
በባለጠግነታቸውም ፡ ብዛት ፡ የሚመኩ ፤
፯፤ ወንድም ፡ ወንድሙን ፡ አያድንም ÷ ሰውም ፡ አያድንም ፤
ቤዛውን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አይሰጥም ÷
፰፱፤ ለዘላለም ፡ እንዲኖር ÷ ጥፋትንም ፡ እንዳያይ ፤
የነፍሳቸው ፡ ለውጥ ፡ ከብሮአልና ÷
ለዘላለምም ፡ ቀርቶአልና ።
፲፤ ብልሃተኞች ፡ እንዲሞቱ ÷
ሰነፎችና ፡ ደንቆሮች ፡ በአንድነት ፡ እንዲጠፉ ÷
ገንዘባቸውንም ፡ ለሌሎች ፡ እንዲተዉ ፡ አይቶአል ።
፲፩፤ በልባቸውም ፡ ቤታቸው ፡ ለዘላለም ፡ የሚኖር ÷
ማደሪያቸውም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ የሚሆን ፡ ይመስላቸዋል ፤
በየአገራቸውም ፡ ስማቸው ፡ ይጠራል ።
፲፪፤ ሰው ፡ ግን ፡ ክቡር ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ አያውቅም ፤
እንደሚጠፉ ፡ እንስሶች ፡ መሰለ ።
፲፫፤ ይህች ፡ መንገዳቸው ፡ መሰናክላቸው ፡ ናት ÷
ከእነርሱም ፡ በኋላ ፡ የሚመጡ ፡ በአፋቸው ፡ እሺ ፡ ይላሉ ።
፲፬፤ እንደ ፡ በጎች ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ የሚሄዱ ፡ ናቸው ÷
እረኛቸውም ፡ ሞት ፡ ነው ፤
ቅኖችም ፡ በማለዳ ፡ ይገዙአቸዋል ÷
ውበታቸውም ፡ ከመኖሪያቸው ፡ ተለይታ ፡ በሲኦል ፡ ታረጃለች ።
፲፭፤ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቀበለኛልና ፡
ነፍሴን ፡ ከሲኦል ፡ እጅ ፡ ይቤዣታል ።
፲፮፤ የሰው ፡ ባለጠግነት ፡ የቤቱም ፡ ክብር ፡ በበዛ ፡ ጊዜ ፡ አትፍራ ÷
፲፯፤ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ምንም ፡ አይወስድምና ÷
ክብሩም ፡ ከእርሱ ፡ በኋላ ፡ አይወርድምና ።
፲፰፤ በሕይወቱ ፡ ሳለ ፡ ነፍሱን ፡ ባርኮአልና ፡
ለሰውነቱ ፡ መልካም ፡ ብታደርግለት ፡ ያመሰግንሃል ።
፲፱፤ ሆኖም ፡ ወደ ፡ አባቶቹ ፡ ትውልድ ፡ ይወርዳል ፤
ለዘላለም ፡ ብርሃንን ፡ አያይም ።
፳፤ አእምሮ ፡ የሌለው ፡ ክቡር ፡ ሰው ፡
እንደሚጠፉ ፡ እንስሶች ፡ መሰለ ።

## መዝሙር ፡ ፵፱ ። (፶)

የአሳፍ ፡ መዝሙር ።

፩፤ የአማልክት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናገረ ÷
ከፀሐይም ፡ መውጫ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ መግቢያዋ ፡ ድረስ ፡ ምድርን ፡ ጠራት ።
፪፤ ከክብሩ ፡ ውበት ፡ ከጽዮን ፡
እግዚአብሔር ፡ ግልጥ ፡ ሆኖ ፡ ይመጣል ።
፫፤ አምላካችን ፡ ይመጣል ፡ ዝምም ፡ አይልም ፤
እሳት ፡ በፊቱ ፡ ይቃጠላል ÷
በዙሪያውም ፡ ብዙ ፡ ዐውሎ ፡ አለ ።
፬፤ በላይ ፡ ያለውን ፡ ሰማይን ፡
ምድርንም ፡ በሕዝቡ ፡ ለመፍረድ ፡ ይጠራል ፤
፭፤ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ለመሥዋዕት ፡ ኪዳን ፡ የቆሙትን ፡
ቅዱሳኑን ፡ ሰብስቡለት ።
፮፤ ሰማያት ፡ ጽድቁን ፡ ይናገራሉ ÷
እግዚአብሔር ፡ ፈራጅ ፡ ነውና ።
፯፤ ሕዝቤ ÷ ስማኝ ÷ ልንገርህ ፤
እስራኤልም ÷ ስማኝ ÷ ልመስክርብህ ፤
አምላክስ ፡ እኔ ፡ አምላክህ ፡ ነኝ ።
፰፤ ስለ ፡ ቍርባንህ ፡ የምዘልፍህ ፡ አይደለሁም ፤
የሚቃጠል ፡ መሥዋዕትህ ፡ ሁልጊዜ ፡ በፊቴ ፡ ነው ።
፱፤ ከቤትህ ፡ ፍሪዳን ፡
ከመንጋህም ፡ አውራ ፡ ፍየልን ፡ አልወስድም ፤
፲፤ የምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ፡
በሺህ ፡ ተራራዎች ፡ ያሉ ፡ እንስሶችም ፡ የእኔ ፡ ናቸውና ።
፲፩፤ የሰማይን ፡ አዕዋፍ ፡ ሁሉ ፡ አውቃለሁ ÷
የምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊትም ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ናቸው ።
፲፪፤ ብራብም ፡ ለአንተ ፡ አልነግርህም ÷
ዓለምና ፡ ሞላው ፡ የእኔ ፡ ነውና ።
፲፫፤ የፍሪዳውን ፡ ሥጋ ፡ እበላለሁን ?
የፍየሉንስ ፡ ደም ፡ እጠጣለሁን ?
፲፬፤ ለእግዚአብሔር ፡ የምስጋናን ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዋ ÷
ለልዑልም ፡ ስእለትህን ፡ ስጥ ፤
፲፭፤ በመከራ ፡ ቀን ፡ ጥራኝ ÷
አድንህማለሁ ፡ አንተም ፡ ታከብረኛለህ ።
፲፮፤ ኃጢአተኛውን ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ አለው ፡—
ለምን ፡ አንተ ፡ ሕጌን ፡ ትናገራለህ ?
ኪዳኔንም ፡ በአፍህ ፡ ለምን ፡ ትወስዳለህ ?
፲፯፤ አንተስ ፡ ተግሣጼን ፡ ጠላህ ÷
ቃሎቼንም ፡ ወደ ፡ ኋላህ ፡ ጣልህ ።
፲፰፤ ሌባውን ፡ ባየህ ፡ ጊዜ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ትሮጥ ፡ ነበር ፡
እድል ፡ ፈንታህንም ፡ ከአመንዝሮች ፡ ጋር ፡ አደረግህ ።
፲፱፤ አፍህ ፡ ክፋትን ፡ አበዛ ÷
አንደበትህም ፡ ሽንገላን ፡ ተበተበ ።
፳፤ ተቀምጠህ ፡ ወንድምህን ፡ አማኸው ÷
ለእናትህም ፡ ልጅ ፡ ዕንቅፋት ፡ አኖርህ ።

፳፩ ይህን ፡ አድርገህ ፡ ዝም ፡ አልሁህ ፤
እኔ ፡ እንደ ፡ አንተ ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ ጠረጠርህ ፤
እዘልፍሃለሁ ፡ በፊትህም ፡ እቆማለሁ ።

፳፪ እግዚአብሔርን ፡ የምትረሱ ፡ እናንተ ÷ ይህን ፡ አስተውሉ ፤
አለዚያ ፡ ግን ፡ ይነጥቃል ፡ የሚያድንም ፡ የለም ።

፳፫ ምስጋናን ፡ የሚሠዋ ፡ ያከብረኛል ፤
የእግዚአብሔርን ፡ ማዳን ፡ ለእርሱ ፡ የማሳይበት ፡ መንገድ ፡ ከዚያ ፡ አለ ።

## መዝሙር ፡ ፶ ። ( ፶፩ )

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ ወደ ፡ ቤርሳቤህ ፡ ከገባ ፡ በኋላ ፡ ነቢዩ ፡ ናታን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ÷ እንደ ፡ ቸርነትህ ፡ መጠን ፡ ማረኝ ፤
እንደ ፡ ምሕረትህም ፡ ብዛት ፡ መተላለፌን ፡ ደምስስ ።

፪ ከበደሌ ፡ ፈጽሞ ፡ እጠበኝ ÷
ከኀጢአቴም ፡ አንጻኝ ፤

፫ እኔ ፡ መተላለፌን ፡ አውቃለሁና ÷
ኀጢአቴም ፡ ሁልጊዜ ፡ በፊቴ ፡ ነውና ።

፬ አንተን ፡ ብቻ ፡ በደልሁ ÷
በፊትህም ፡ ክፋትን ፡ አደረግሁ ÷
በነገርህ ፡ ትጸድቅ ፡ ዘንድ ፡ በፍርድህም ፡ ንጹሕ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ።

፭ እነሆ ÷ በዓመፃ ፡ ተፀነስሁ ÷
እናቴም ፡ በኀጢአት ፡ ወለደችኝ ።

፮ እነሆ ÷ እውነትን ፡ ወደድህ ፤
የማይታይ ፡ ስውር ፡ ጥበብን ፡ አስታወቅኸኝ ።

፯ በሂሶጵ ፡ እርጨኝ ÷ እነጻማለሁ ፤
እጠበኝ ÷ ከበረዶም ፡ ይልቅ ፡ ነጭ ፡ እሆናለሁ ።

፰ ሐሤትንና ፡ ደስታን ፡ አሰማኝ ÷
የሰበርሃቸውም ፡ አጥንቶቼ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።

፱ ከኀጢአቴ ፡ ፊትህን ፡ መልስ ÷
በደሌንም ፡ ሁሉ ፡ ደምስስልኝ ።

፲ አቤቱ ÷ ንጹሕ ፡ ልብን ፡ ፍጠርልኝ ÷
የቀናውንም ፡ መንፈስ ፡ በውስጤ ፡ አድስ ።

፲፩ ከፊትህ ፡ አትጣለኝ ÷
ቅዱስ ፡ መንፈስህንም ፡ ከእኔ ፡ ላይ ፡ አትውሰድብኝ ።

፲፪ የማዳንህን ፡ ደስታ ፡ ስጠኝ ÷
በእሽታ ፡ መንፈስም ፡ ደግፈኝ ።

፲፫ ለሕግ ፡ ተላላፎች ፡ መንገድህን ፡ አስተምራለሁ ÷
ኀጢአተኞችም ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ይመለሳሉ ።

፲፬ የመድኀኒቴ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ÷ ከደም ፡ አድነኝ ÷
አንደበቴም ፡ በአንተ ፡ ጽድቅ ፡ ትደሰታለች ።

፲፭ አቤቱ ÷ ከንፈሮቼን ፡ክፈት ÷
አፌም ፡ ምስጋናህን ፡ ያወራል ።

፲፮ መሥዋዕትን ፡ ብትወድድስ ፡ በሰጠሁህ ፡ ነበር ፤
የሚቃጠለውም ፡ መሥዋዕት ፡ ደስ ፡ አያሰኝህም ።

፲፯ የእግዚአብሔር ፡ መሥዋዕት ፡ የተሰበረ ፡ መንፈስ ፡ ነው ÷
የተሰበረውንና ፡ የተዋረደውን ፡ ልብ ፡ እግዚአብሔር ፡ አይንቅም ።

፲፰ አቤቱ ÷ በውዴታህ ፡ ጽዮንን ፡ አሰማምራት ፤
የኢየሩሳሌምንም ፡ ቅጽሮች ፡ሥራ ።

፲፱ የጽድቁን ፡ መሥዋዕት ፡
መባውንም ፡ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ በወደድህ ፡ ጊዜ ÷
ያን ፡ ጊዜ ፡ በመሠዊያህ ፡ ላይ ፡ ፍሪዳዎችን ፡ ይሠዋሉ ።

## መዝሙር ፡ ፶፩ ። ( ፶፪ )

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ ኤዶማዊው ፡ ዶይቅ ፡ መጥቶ ፡ ለሳኦል ፡— ዳዊት ፡ ወደ ፡ አቢሜሌክ ፡ ቤት ፡ መጥቶ ፡ አል ፡ ብሎ ፡ በነገረው ፡ ጊዜ ፤ የዳዊት ፡ ትምህርት ።

፩ ኃያል ፡ ሆይ ÷ በክፋት ፡ ለምን ፡ ትጓደዳለህ ?
ሁልጊዜስ ፡ በመተላለፍ ?

፪ አንደበትህ ፡ ኀጢአትን ፡ ያስባል ፤
እንደ ፡ ተሳለ ፡ ምላጭ ፡ሽንገላን ፡ አደረግህ ።

፫ ከመልካም ፡ ይልቅ ፡ ክፋትን ÷
ጽድቅንም ፡ ከመናገር ፡ ይልቅ ፡ ዓመፃን ፡ ወደድህ ።

፬ የሚያጠፋ ፡ ቃልን ፡ ሁሉ ÷ የሽንገላ ፡ ምላስን ፡ ወደድህ ።

፭ ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ያፈርስሃል ፤
ከቤትህም ፡ ይነቅልሃል ፡ ያፈልስሃልም ÷
ሥርህንም ፡ ከሕያዋን ፡ ምድር ።

፮ ጻድቃን ፡ አይተው ፡ ይፈራሉ ፤
በእርሱም ፡ ይሥቃሉ ፡ እንዲህም ፡ ይላሉ ፡—

፯ እግዚአብሔርን ፡ ረዳቱ ፡ ያላደረገ ÷
በባለጠግነቱም ፡ ብዛት ፡ የታመነ ÷
በከንቱ ፡ ነገርም ፡ የበረታ ፡ ያ ፡ ሰው ፡ እነሆ ።

፰ እኔስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ለመለመ ፡ እንደ ፡ ወይራ ፡ ዛፍ ፡ ነኝ ፤
ለዓለምና ፡ ለዘላለም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ምሕረት ፡ ታመንሁ ።

፱ አድርገህልኛልና ፡ ለዘላለም ፡ አመሰግንሃለሁ ÷
በቅዱሳንህም ፡ ዘንድ ፡ መልካም ፡ ነውና ፡ ስምህን ፡ ተስፋ ፡ አደርጋለሁ ።

## መዝሙር ፡ ፶፪ ። ( ፶፫ )

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በማኸላት ፤ የዳዊት ፡ ትምህርት ።

፩ ሰነፍ ፡ በልቡ ፡— አምላክ ፡ የለም ፡ ይላል ።
ረከሱ ፡ በበደላቸውም ፡ ጐሰቈሉ ፤
በጎ ፡ ነገርን ፡ የሚያደርጋት ፡ የለም ።

፪ የሚያስተውል ፡ እግዚአብሔርንም ፡ የሚፈልግ ፡ እንዳለ ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡
እግዚአብሔር ፡ ከሰማይ ፡ የሰው ፡ ልጆችን ፡ ተመለከተ ።

፫ ሁሉ ፡ በደሉ ÷ አብረውም ፡ ረከሱ ፤
አንድ ፡ስንኳ ፡ በጎን ፡ ነገር ፡ የሚያደርጋት ፡ የለም ።

፬ ሕዝቤን ፡ እንጀራ ፡ እንደሚበላ ፡ የሚበሉ ፡
ግፍ ፡ አድራጊዎች ፡ ሁሉ ፡ አያውቁምን ?
እግዚአብሔርንም ፡ አይጠሩትም ።

፭፤ እግዚአብሔር ፡ የግብዞችን ፡ አጥንቶች ፡ በትኖ አልና ፡
በዚያ ፡ የሚያስፈራ ፡ ሳይኖር ፡ እጅግ ፡ ፈሩ ፤
እግዚአብሔር ፡ ንቆአቸዋልና ፡ አሳፈርሃቸው ።
፮፤ መድኃኒትን ፡ ከጽዮን ፡ ለእስራኤል ፡ ማን ፡ በሰጠ !
እግዚአብሔር ፡ የሕዝቡን ፡ ምርከ ፡ በመለሰ ፡ ጊዜ ÷
ያዕቆብ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡ እስራኤልም ፡ ሐሤት ፡ ያደርጋል ።

## መዝሙር ፡ ፶፫ ። (፶፬)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በበገናዎች ፤ ዜፋውያን ፡ መጥተው ፡ ለሳኦል ፡— እነሆ ፡ ዳዊት ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ ተሸሽጓል ፡ ብለው ፡ በነገሩት ፡ ጊዜ ፤ የዳዊት ፡ ትምህርት ።

፩፤ አቤቱ ÷ በስምህ ፡ አድነኝ ÷
በኃይልህም ፡ ፍረድልኝ ።
፪፤ አቤቱ ÷ ጸሎቴን ፡ ስማኝ ÷
የአፌንም ፡ ቃል ፡ አድምጥ ፤
፫፤ እንግዶች ፡ ቁመውብኛልና ÷
ኃያላንም ፡ ነፍሴን ፡ሽተዋታልና ።
እግዚአብሔርን ፡ በፊታቸው ፡ አላደረጉትም ።
፬፤ እነሆ ÷ እግዚአብሔር ፡ ይረዳኛል ÷
ጌታዬም ፡ ለነፍሴ ፡ ደጋፊዋ ፡ ነው ።
፭፤ ክፋትን ፡ ወደ ፡ ጠላቶቼ ፡ ይመልሳታል ፤
በእውነትህም ፡ አጥፋቸው ።
፮፤ ከፈቃዴ ፡ እሠዋልሃለሁ ፤
አቤቱ ÷ መልካም ፡ ነውና ፡ ስምህን ፡ አመሰግናለሁ ፤
፯፤ ከመከራ ፡ ሁሉ ፡ አድኖኛልና ÷
ዓይኔም ፡ በጠላቶቼ ፡ ላይ ፡ አይታለችና ።

## መዝሙር ፡ ፶፬ ። (፶፭)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በበገናዎች ፤
የዳዊት ፡ ትምህርት ።

፩፤ አቤቱ ÷ ጸሎቴን ፡ አድምጥ ÷
ልመናዬንም ፡ ቸል ፡ አትበል ።
፪፤ ተመልከተኝ ፡ ስማኝም ፤
በኀዘኔ ፡ ተቅበዘበዝሁ ፡ ተናወጥሁም ፤
፫፤ ከጠላት ፡ ድምፅ ፡ ከዓመፀኛም ፡ ግፍ ፡ የተነሣ ፤
ዓመፃን ፡ በላዬ ፡ ጥለውብኛልና ÷ በቍጣም ፡ ጠልተውኛልና ።
፬፤ ልቤ ፡ በላዬ ፡ ተናወጠብኝ ÷
የሞት ፡ ድንጋጤም ፡ ወደቀብኝ ።
፭፤ ፍርሃትና ፡ እንቅጥቅጥ ፡ መጡብኝ ÷
ጨለማም ፡ ሸፈነኝ ።
፮፤ በርሬ ፡ ዐርፍ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ርግብ ፡ ክንፍን ፡ ማን ፡ በሰጠኝ !
፯፤ እነሆ ÷ ኰብልዬ ፡ በራቅሁ ፡ በምድረ ፡ በዳም ፡ በተቀመጥሁ ፤
፰፤ ከዐውሎና ፡ ከብርቱ ፡ ንፋስ ፡ ሸሽቼ ፡ በፈጠንሁ ፡ አልሁ ።
፱፤ አቤቱ ÷ ግፍንና ፡ ጠብን ፡ በከተማ ፡ ውስጥ ፡ አይቼአለሁና ፡
አስጥማቸው ፡ እንደበታቸውንም ፡ ቍረጥ ።
፲፤ በቀንና ፡ በሌሊት ፡ በቅጥርዋ ፡ ይከብቡአታል ፤
ዓመፃና ፡ ድካም ፡ ኃጢአትም ፡ በመካከልዋ ፡ ነው ፤
፲፩፤ ተንኰልና ፡ ሽንገላ ፡ ከአደባባይዋ ፡ አይርቁም ።
፲፪፤ ጠላትስ ፡ ቢሰድበኝ ÷ በታገሥሁ ፡ ነበር ፤
የሚጠላኝም ፡ ራሱን ፡ በላዬ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ቢያደርግ ÷
ከእርሱ ፡ በተሸሸግሁ ፡ ነበር ።
፲፫፤ አንተ ፡ ግን ÷ እኩያዬ ፡ ሰው ÷
ባልንጀራዬና ፡ የልቤ ፡ ወዳጅ ፤
፲፬፤ መብልን ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ በአንድነት ፡ ያጣፈጥህ ፤
በአንድ ፡ ልብ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ተራመድን ።
፲፭፤ ሞት ፡ ይምጣባቸው ፤
በሕይወት ፡ ሳሉ ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ይውረዱ ፤
ክፋት ፡ በማደሪያቸውና ፡ በመካከላቸው ፡ ነውና ።
፲፮፤ እኔ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኽሁ ፥
እግዚአብሔርም ፡ሰማኝ ።
፲፯፤ በማታና ፡ በጥዋት ፡ በቀትርም ፡ እናገራለሁ ፡
እጮኻለሁ ÷ ቃሌንም ፡ ይሰማኛል ።
፲፰፤ በእኔ ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ነበሩና ፡
ከሚቃረቡኝ ፡ ነፍሴን ፡ በሰላም ፡ አድናት ።
፲፱፤ ቤዛ ፡ የላቸውምና ÷ እግዚአብሔርንም ፡ አልፈሩትምና ፡
ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ የነበረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰምቶ ፡ ያጐሰቍላቸዋል ።
፳፤ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሰላም ፡ በነበሩት ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ ዘረጋ ፤
ኪዳኑንም ፡ አረከሰ ።
፳፩፤ አፉ ፡ ከቅቤ ፡ ይልቅ ፡ ለዘበ ÷ በልቡ ፡ ግን ፡ ሰልፍ ፡ ነበረ ፤
ቃሎቹም ፡ ከዘይት ፡ ይልቅ ፡ ለሰለሱ ÷
እነርሱ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ተመዘዘ ፡ሰይፍ ፡ ናቸው ።
፳፪፤ ትካዜህን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ጣል ፥
እርሱም ፡ ይደግፍሃል ፤
ለጻድቁም ፡ ለዘላለም ፡ ሁከትን ፡ አይሰጠውም ።
፳፫፤ አንተ ፡ ግን ÷ አቤቱ ÷ ወደ ፡ ሞት ፡ ጕድጓድ ፡ ታወርዳቸዋለህ ፤
የደም ፡ ሰዎችና ፡ ሸንጋዮች ፡ ዘመናቸው ፡ ግማሽ ፡ አይሞላም ፤
እኔ ፡ ግን ÷ አቤቱ ÷ እታመንሃለሁ ።

## መዝሙር ፡ ፶፭ ። (፶፮)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ ከቅዱሳን ፡ ስለ ፡ ራቁ ፡ ሕዝብ ፤ ፍልስጥኤማውያን ፡ በጌት ፡ በያዙት ፡ ጊዜ ፤ የዳዊት ፡ ቅኔ ።

፩፤ አቤቱ ÷ ሰው ፡ ረግጦኛልና ፡ ማረኝ ፤
ሁልጊዜም ፡ በሰልፍ ፡ አስጨንቆኛል ።
፪፤ የሚዋጉኝ ፡ በዝተዋልና ፡
ሁልጊዜ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ጠላቶቼ ፡ ረገጡኝ ።
፫፤ እኔ ፡ ግን ፡ ፈራሁ ፡ በአንተም ፡ ታመንሁ ።
፬፤ በእግዚአብሔር ፡ ቃሉን ፡ አመሰግናለሁ ፤
በእግዚአብሔር ፡ ታመንሁ ÷ አልፈራም ፤ ሰው ፡ ምን ፡ ያደርገኛል ?

፭፡ ሁልጊዜ ፡ ቃሎቼን ፡ ያጸይፋብኛል ፤
በእኔ ፡ ላይም ፡ የሚመከሩት ፡ ሁሉ ፡ ለክፉ ፡ ነው ።
፮፡ ይሸምቁብኛል ፡ ይሸሽጉኝማል ÷
እነርሱም ፡ ተረከዜን ፡ ይመለከከታሉ ÷
ሁልጊዜም ፡ ነፍሴን ፡ ይሸምቁበታል ።
፯፡ በምንም ፡ ምን ፡ አታድናቸውም ፤
አሕዛብን ፡ በቍጣ ፡ ትጥላቸዋለህ ።
፰፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ ሕይወቴን ፡ ነገርሁህ ፤
እንባዬን ፡ እንደ ፡ ትእዛዝህ ፡ በፊተህ ፡ አኖርህ ።
፱፡ በጠራሁህ ፡ ጊዜ ፡ ጠላቶቼ ፡ ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ይመለሳሉ ፤
አንተ ፡ አምላኬ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ እነሆ ÷ አወቅሁ ።
፲፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃሉን ፡ አመሰግናለሁ ፤
በእግዚአብሔር ፡ ቃሉን ፡ አከብራለሁ ።
፲፩፡ በእግዚአብሔር ፡ ታመንሁ ÷ አልፈራም ፤ ሰው ፡ ምን ፡ ያደርገኛል ?
፲፪፡ አቤቱ ÷ የምስጋና ፡ ስእለት ፡ የምሰጥህ ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤
፲፫፡ ነፍሴን ፡ ከሞት ÷ እግሮቼን ፡ ከመውደቅ ፡ አድንሃልና ÷
በሕያዋን ፡ ብርሃን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ እሰኘው ፡ ዘንድ ።

## መዝሙር ፡ ፶፮ ። (፶፯)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ አታጥፋ ። ከሳኦል ፡ ፊት ፡ ሸሽቶ ፡ በዋሻ ፡ በነበረበት ፡ ጊዜ ፤ የዳዊት ፡ ቅኔ ።

፩፡ ማረኝ ÷ አቤቱ ÷ ማረኝ ÷
ነፍሴ ፡ አንተን ፡ ታምናለችና ፤
ጉዳት ፡ እስከታልፍ ፡ ድረስ ፡
በክንፎችህ ፡ ጥላ ፡ እታመናለሁ ።
፪፡ ወደሚረዳኝ ፡ እግዚአብሔር ፡
ወደ ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ እጮኻለሁ ።
፫፡ ከሰማይ ፡ ልኮ ፡ አዳነኝ ÷
ለረገጡኝም ፡ ውርደትን ፡ ሰጣቸው ፤
እግዚአብሔር ፡ ቸርነቱንና ፡ እውነቱን ፡ ላከ ።
፬፡ ነፍሴን ፡ ከአንበሶች ፡ መከከል ፡ አዳናት ።
ደንግጬ ፡ ተኛሁ ፤
የሰው ፡ ልጆች ፡ ጥርሳቸው ፡ ጦርና ፡ ፍላጻ ÷
አንደበታቸው ፡ የተሳለ ፡ ሾተል ፡ ነው ።
፭፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ በሰማያት ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በል ፤
ክብርህም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ትሁን ።
፮፡ ለእግሮቼ ፡ ወጥመድን ፡ አዘጋጁ ÷
ነፍሴንም ፡ አጐበጡአት ፤
ጕድጓድን ፡ በፊቴ ፡ ቈፈሩ ÷ በእርሱም ፡ ወደቁ ።
፯፡ ልቤ ፡ ጨከኝ ፡ ነው ÷ አቤቱ ÷ ልቤ ፡ ጨከኝ ፡ ነው ፤
እቀኛለሁ ÷ እዘምራለሁ ።
፰፡ ክብሬ ፡ ይነሣ ÷
በገናና ፡ መሰንቆም ፡ ይነሡ ፤
እኔም ፡ ማልጄ ፡ እነሣለሁ ።
፱፡ አቤቱ ÷ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ አመሰግንሃለሁ ÷
በወገኖችም ፡ ዘንድ ፡ እዘምርልሃለሁ ፤
፲፡ ምሕረትህ ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ድረስ ፡ ከፍ ፡ ብላለችና ÷
እውነትህም ፡ እስከ ፡ ደመናት ፡ ድረስ ።
፲፩፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ በሰማያት ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በል ፤
ክብርህም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ትሁን ።

## መዝሙር ፡ ፶፯ ። (፶፰)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ አታጥፋ ። የዳዊት ፡ ቅኔ ።

፩፡ በእውነት ፡ ጽድቅን ፡ ብትናገሩስ ÷
የሰው ፡ ልጆች ፡ ሆይ ÷ በቅን ፡ ትፈርዳላችሁ ፤
፪፡ በልባችሁ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ኃጢአትን ፡ ትሠራላችሁና ÷
እጆቻችሁም ፡ ግፍን ፡ ይታታሉና ።
፫፡ ኀጥአን ፡ ከማሕፀን ፡ ጀምረው ፡ ተለዩ ፤
ከሆድም ፡ ጀምረው ፡ ሳቱ ÷ ሐሰትንም ፡ ተናገሩ ።
፬፡ ቍጣቸው ፡ እንደ ፡ እባብ ፡ መርዝ ፡ ነው ÷
እንደ ፡ ምድር ፡ እውሬም ፡ ጆሮዋ ፡ የተደፈነ ፡ ነው ÷
፭፡ እዋቂ ፡ ሲደግምበት ፡ የአስማተኛውን ፡ ቃል ፡ እንደማትሰማ ።
፮፡ እግዚአብሔር ፡ ጥርሳቸውን ፡ በአፋቸው ፡ ውስጥ ፡ ይሰብራል ፤
እግዚአብሔር ፡ የአንበሶቹን ፡ መንጋጋቸውን ፡ ያደቅቃል ።
፯፡ እንደሚፈስስ ፡ ውኃ ፡ ይቀልጣሉ ፤
እስኪያደክማቸው ፡ ድረስ ፡ ፍላጻቹን ፡ ይገትራል ።
፰፡ እንደሚቀልጥ ፡ ሰም ፡ ያልቃሉ ፤
እሳት ፡ ወደቀች ÷ ፀሐይንም ፡ አላዩአትም ።
፱፡ እሾኻችሁ ፡ ሳይታወቅ ፡ በትር ፡ ሆነ ፤
ሕያዋን ፡ ሳላችሁ ፡ በመዓቱ ፡ ይነጥቃችኋል ።
፲፡ ጻድቅ ፡ በቀልን ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤
በኃጢአተኛው ፡ ደምም ፡ እጁን ፡ ይታጠባል ።
፲፩፡ ሰውም ፡— በእውነት ፡ ለጻድቅ ፡ ፍሬ ፡ አለው ፤
በእውነት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የሚፈርድ ፡ አምላክ ፡ አለ ፡ ይላል ።

## መዝሙር ፡ ፶፰ ። (፶፱)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ አታጥፋ ። ሳኦል ፡ ይገድሉት ፡ ዘንድ ፡ቤቱን ፡ እንዲጠብቁ ፡ በላከ ፡ ጊዜ ፤ የዳዊት ፡ ቅኔ ።

፩፡ አምላኬ ፡ ሆይ ÷ ከጠላቶቼ ፡ አድነኝ ፤
በላዬም ፡ ከቆሙት ፡ አስጥለኝ ።
፪፡ ከግፍ ፡ አድራጊዎች ፡ ታደገኝ ÷
ከደም ፡ ሰዎችም ፡ አድነኝ ።
፫፡ እነሆ ÷ ነፍሴን ፡ ሸምቀውባታልና ÷
ብርቱዎችም ፡ በላዬ ፡ ተሰበሰቡ ፤
አቤቱ ÷ በበደሌም ፡ አይደለም ÷ በኃጢአቴም ፡ አይደለም ።
፬፡ ያለ ፡ በደል ፡ሮጥሁ ፡ ተዘጋጀሁም ፤
ተነሥ ÷ ተቀበለኝ ÷ እይም ።
፭፡ አንተም ፡ አቤቱ ÷ የኃያላን ፡ አምላክ ÷ የእስራኤል ፡ አምላክ ÷
አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ ትጐበኛቸው ፡ ዘንድ ፡ ተነሥ ፤
ዓመፅ ፡ የሚያደርጉትን ፡ ሁሉ ፡ አትማራቸው ።
፮፡ ማታ ፡ ይመለሱ ፡ እንደ ፡ ውሾችም ፡ ይራቡ ÷

በከተማም ፡ ይዞሩ ።
፯ ፤ እነሆ ፥ በአፋቸው ፡ አሰምተው ፡ ይናገራሉ ፤
ሰይፍም ፡ በከንፈሮቻቸው ፡ አለ ፤
ማን ፡ ይሰማል ? ይላሉ ።
፰ ፤ አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፥ ትሥቅባቸዋለህ ፥
አሕዛብንም ፡ ሁሉ ፡ ትንቃቸዋለህ ።
፱ ፤ እግዚአብሔር ፡ መጠጊያዬ ፡ ነውና ፡
ኃይሌን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ አስጠጋለሁ ።
፲ ፤ የአምላኬ ፡ ቸርነቱ ፡ ይገናኘኛል ፡
አምላኬ ፡ በጠላቶቼ ፡ ላይ ፡ ያሳየኛል ።
፲፩ ፤ ሕዝቤ ፡ እንዳይረሱ ፡ አትግደላቸው ፤
አቤቱ ፡ ጋሻዬ ፥ በኃይልህ ፡ በትናቸው ፡ አውርዳቸውም ።
፲፪ ፤ ስለ ፡ አፋቸው ፡ ኃጢአት ፡ ስለ ፡ ከንፈራቸውም ፡ ቃል ፥
መርገምንና ፡ ሐሰትን ፡ ስለሚናገሩ ፥
በትዕቢታቸው ፡ ይጠመዱ ።
፲፫ ፤ በቍጣ ፡ አጥፋቸው ፥ እንዳይኖሩም ፡ አጥፋቸው ፤
የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ እንዲገዛ ፡ ይወቁ ።
፲፬ ፤ ማታ ፡ ይመለሱ ፡ እንደ ፡ ውሾችም ፡ ይራቡ ፥
በከተማም ፡ ይዞሩ ።
፲፭ ፤ እነርሱም ፡ መብል ፡ ለመፈለግ ፡ ይበተኑ ፤
ያልጠገቡ ፡ እንደ ፡ ሆነም ፡ ያንጐራጕራሉ ።
፲፮ ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ለኃይልህ ፡ እቀኛለሁ ፤
በምሕረትህም ፡ ማልዶ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፤
በመከራዬ ፡ ቀን ፡ መጠጊያዬና ፡ አምባዬ ፡ ሆንኸኛልና ።
፲፯ ፤ ረዳቴ ፡ ሆይ ፥ ለአንተ ፡ ለአምላኬ ፡ እዘምራለሁ ፤
አንተ ፥ አምላኬ ፥ መጠጊያዬ ፡ ምሕረቴም ፡ ነህና ።

## መዝሙር ፡ ፶፱ ። (፷)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የሶርያን ፡ ሁለቱን ፡ ወንዞችና ፡ የሶርያን ፡ ሶባልን ፡ ባቃጠለ ፡ ጊዜ ፡ ኢዮአብም ፡ ተመልሶ ፡ ከኤዶማውያን ፡ ሰዎች ፡ በጨው ፡ ሸለቆ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ በገደለ ፡ ጊዜ ፤ ለትምህርት ፡ የዳዊት ፡ ቅኔ ።

፩ ፤ አቤቱ ፥ ጣልኸን ፡ አፈረስኸንም ፤
ተቈጣኸን ፡ ይቅርም ፡ አልኸን ።
፪ ፤ ምድርን ፡ አናወጥሃት ፡ አወከሃትም ፤
ተናውጣለችና ፡ ቍስልዋን ፡ ፈውስ ።
፫ ፤ ለሕዝብህ ፡ ጭንቅን ፡ አሳየሃቸው ፥
አስደንጋጩንም ፡ ወይን ፡ አጠጣኸን ።
፬ ፤ ከቀስት ፡ ፊት ፡ ያመልጡ ፡ ዘንድ ፥
ለሚፈሩህ ፡ ምልክትን ፡ ሰጠሃቸው ።
፭ ፤ ወዳጆችህ ፡ እንዲድኑ ፡
በቀኝህ ፡ አድን ፥ አድምጠኝም ።
፮ ፤ እግዚአብሔር ፡ በቅድስናው ፡ ተናገረ ፤
ደስ ፡ ይለኛል ፥ ሴኬምንም ፡ እካፈላለሁ ፥
የሱኮትንም ፡ ሸለቆ ፡ እሰፍራለሁ ።
፯ ፤ ገለዓድ ፡ የእኔ ፡ ነው ፥ ምናሴም ፡ የእኔ ፡ ነው ፤
ኤፍሬም ፡ የራሴ ፡ መጠጊያ ፡ ነው ።
ይሁዳ ፡ ንጉሤ ፡ ነው ፤
፰ ፤ ሞዓብ ፡ መታጠቢያዬ ፡ ነው ፥
በኤዶምያስ ፡ ላይ ፡ ጫማዬን ፡ እዘረጋለሁ ፤
ፍልስጥኤም ፡ ይገዙልኛል ።
፱ ፤ ወደ ፡ ጽኑ ፡ ከተማ ፡ ማን ፡ ይወስደኛል ?
ማንስ ፡ እስከ ፡ ኤዶምያስ ፡ ይመራኛል ?
፲ ፤ አቤቱ ፥ የጣልኸን ፡ አንተ ፡ አይደለህምን ?
አምላክ ፡ ሆይ ፥ ከሠራዊታችን ፡ ጋር ፡ አትወጣም ።
፲፩ ፤ በመከራችን ፡ ረድኤትን ፡ ስጠን ፥
የሰውም ፡ ማዳን ፡ ከንቱ ፡ ነው ።
፲፪ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ኃይልን ፡ እናደርጋለን ፤
እርሱ ፡ የሚያስጨንቁንን ፡ ያዋርዳቸዋልና ።

## መዝሙር ፡ ፷ ። (፷፩)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በበገናዎች ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ ፤ አምላክ ፡ ሆይ ፥ ልመናዬን ፡ ስማ ፥
ጸሎቴንም ፡ አድምጥ ።
፪ ፤ ልቤ ፡ ተስፋ ፡ በቈረጠ ፡ ጊዜ ፡ ከምድር ፡ ዳርቻ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እጮኻለሁ ፤
በድንጋይ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረግኸኝ ።
፫ ፤ ጽኑ ፡ ግንብ ፡ በጠላት ፡ ፊት ፡
ተስፋዬም ፡ ሆንኸኛልና ፡ መራኸኝ ።
፬ ፤ በድንኳንህ ፡ ለዘላለም ፡ እኖራለሁ ፤
በክንፎችህም ፡ ጥላ ፡ እጋረዳለሁ ፤
፭ ፤ አቤቱ ፥ አንተ ፡ ስእለቴን ፡ ሰምተሃልና ፤
ስምህንም ፡ ለሚፈሩ ፡ ርስትን ፡ ሰጠሃቸው ።
፮ ፤ ለንጉሥ ፡ ከቀን ፡ በላይ ፡ ቀን ፡ ትጨምራለህ ፥
ዓመታቱም ፡ ከትውልድ ፡ ወደ ፡ ትውልድ ፡ ይሆናሉ ።
፯ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ፤
ይጠብቁት ፡ ዘንድ ፡ ምሕረትንና ፡ እውነትን ፡ አዘጋጅለት ።
፰ ፤ እንዲሁ ፡ ለስምህ ፡ ለዘላለም ፡ እዘምራለሁ ፡
ስእለቴን ፡ ሁልጊዜ ፡ እፈጽም ፡ ዘንድ ።

## መዝሙር ፡ ፷፩ ። (፷፪)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ ስለ ፡ ኤዶታም ፤
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ ፤ ነፍሴ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የምትገዛ ፡ አይደለችምን ?
መድኃኒቴ ፡ ከእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ናትና ።
፪ ፤ እርሱ ፡ አምላኬ ፡ መድኃኒቴም ፡ ነውና ፤
እርሱ ፡ መጠጊያዬ ፡ ነው ፥ እጅግም ፡ አልታወክም ።
፫ ፤ እስከ ፡ መቼ ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ትቆማላችሁ ?
እናንተ ፡ ሁላችሁ ፡ እንዳዘነበለ ፡ ግድግዳ ፡
እንደ ፡ ፈረሰም ፡ ቅጥር ፡ ትገድላላችሁ ።
፬ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ክብሬን ፡ ይሽሩ ፡ ዘንድ ፡ መከሩ ፥
ሐሰትንም ፡ ይወድዳሉ ፤
በአፋቸው ፡ ይባርካሉ ፥ በልባቸውም ፡ ይረግማሉ ።

፮፤ ነገር ፡ ግን ÷ ነፍሴ ፡ ሆይ ÷ አንቺ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተገዢ ÷
ተስፋዬ ፡ ከእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ናትና ።
፯፤ እርሱ ፡ አምላኬ ፡ መድኃኒቴም ፡ ነውና ፤
እርሱ ፡ መጠጊያዬ ፡ ነው ፤ አልታወክም ።
፰፤ መድኃኒቴና ፡ ክብሬ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ነው ፤
የረድኤቴ ፡ አምላክ ፡ ተስፋዬም ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ።
፱፤ የሕዝብ ፡ ማኅበር ፡ ሁላችሁ ÷ በእርሱ ፡ ታመኑ ÷
ልባችሁንም ፡ በፊቱ ፡ አፍስሱ ፤
እግዚአብሔር ፡ ረዳታችን ፡ ነው ።
፲፤ ነገር ፡ ግን ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ከንቱ ፡ ናቸው ÷
የሰው ፡ ልጆችም ፡ ሐሰተኞች ፡ ናቸው ፤
በሚዛንም ፡ ይበድላሉ ÷
እነርሱስ ፡ በፍጹም ፡ ከንቱ ፡ ናቸው ።
፲፩፤ ዓመፃን ፡ ተስፋ ፡ አታድርጉ ÷
ቅሚያንም ፡ አትተማመኑት ፤
በለጠግነት ፡ ቢበዛ ፡ ልባችሁ ፡ አይከተል ።
፲፪፤ እግዚአብሔር ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ተናገረ ÷
እኔም ፡ ይህን ፡ ብቻ ፡ ሰማሁ ፤
ኃይል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነው ÷
፲፫፤ አቤቱ ÷ ምሕረትም ፡ ያንተ ፡ ነው ፤
አንተ ፡ ለእያንዳንዱ ፡ እንደ ፡ ሥራው ፡ ፍዳውን ፡ ትሰጣለህና ።

## መዝሙር ፡ ፷፪ ። (፷፫)

በኤዶምያስ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፤
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አምላኬ ÷ አምላኬ ÷ ወደ ፡ አንተ ፡ እገሠግሣለሁ ፤
ነፍሴ ፡ አንተን ፡ ተጠማች ÷
ሥጋዬ ፡ አንተን ፡ እንዴት ፡ ናፈቀች ፡
እንጨትና ፡ ውኃ ፡ በሌለበት ፡ በምድረ ፡ በዳ ።
፪፤ ኃይልህንና ፡ ክብርህን ፡ አይ ፡ ዘንድ ፡
እንዲሁ ፡ በመቅደስ ፡ ውስጥ ፡ ተመለከትሁህ ።
፫፤ ምሕረትህ ፡ ከሕይወት ፡ ይሻላልና ፡
ከንፈሮቼ ፡ ያመሰግኑሃል ።
፬፤ እንዲህ ፡ በሕይወቴ ፡ ዘመን ፡ አመሰግንሃለሁ ÷
በአንተም ፡ ስም ፡ እጆቼን ፡ አነሣለሁ ።
፭፤ ነፍሴ ፡ በቅቤና ፡ በስብ ፡ እንደሚጠግቡ ፡ ትጠግባለች ÷
ከንፈሮቼም ፡ ስምህን ፡ በደስታ ፡ ያመሰግናሉ ።
፮፤ በመኝታዬም ፡ አስብሃለሁ ÷
በማለዳም ፡ እናገርልሃለሁ ፤
፯፤ ረዳቴ ፡ ሆነኸኛልና ÷
በክንፎችህም ፡ ጥላ ፡ ደስ ፡ ይለኛልና ።
፰፤ ነፍሴ ፡ በኋላህ ፡ ተከታተለች ÷
እኔንም ፡ ቀኝህ ፡ ተቀበለችኝ ።
፱፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ ነፍሴን ፡ ለከንቱ ፡ ፈለጓት ፤
ወደ ፡ ምድር ፡ ጥልቅ ፡ ይገባሉ ።
፲፤ ለሰይፍ ፡ እጅ ፡ አልፈው ፡ ይሰጣሉ ÷
የቀበሮም ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ ይሆናሉ ።
፲፩፤ ንጉሥ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤
በእርሱ ፡ የሚምል ፡ ሁሉ ፡ ይከብራል ÷
ሐሰትን ፡ የሚናገር ፡ አፍ ፡ ይዘጋልና ።

## መዝሙር ፡ ፷፫ ። (፷፬)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ÷ ወደ ፡ አንተ ፡ በለመንሁ ፡ ጊዜ ፡ ጸሎቴን ፡ ስማኝ ÷
ከጠላትም ፡ ፍርሃት ፡ ነፍሴን ፡ አድን ።
፪፤ ከክፉዎች ፡ ሸንጎ ፡
ከዓመፀኞችም ፡ ብዛት ፡ ሰውረኝ ።
፫፤ እንደ ፡ ሰይፍ ፡ ምላሳቸውን ፡ አሰሉ ፤
መራራ ፡ ነገርን ፡ ለማድረግ ÷
፬፤ ንጹሕንም ፡ በስውር ፡ ለመንደፍ ፡ ቀስትን ፡ ገተሩ ፤
ድንገት ፡ ይነድፉታል ፡ አይፈሩምም ።
፭፤ ለእነርሱ ፡ ለራሳቸው ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ አጸኑ ፤
ወጥመድን ፡ ይሰውሩ ፡ ዘንድ ፡ ተማከሩ ፤
ማንስ ፡ ያየናል ? ይላሉ ።
፮፤ ዓመፃን ፡ ፈለጓት ÷
ሲፈትኑም ፡ አለቁ ፤
የሰው ፡ የውስጥ ፡ አሳቡና ፡ ልቡ ፡ የጠለቀ ፡ ነው ÷
፯፤ እግዚአብሔርም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
የድንገትም ፡ ፍላጻ ፡ ያቈስላቸዋል ፤
፰፤ አንደበታቸው ፡ ያሰናክላቸዋል ÷
የሚያዩአቸውም ፡ ሁሉ ፡ ይደነግጣሉ ።
፱፤ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ፈሩ ÷
የእግዚአብሔርንም ፡ ሥራ ፡ ተናገሩ ÷
ሥራውንም ፡ አስተዋሉ ።
፲፤ ጻድቅ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይለዋል ÷ በእርሱም ፡ ይታመናል ፤
ልባቸውም ፡ የቀና ፡ ሁሉ ፡ እልል ፡ ይላሉ ።

## መዝሙር ፡ ፷፬ ። (፷፭)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የዳዊት ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ÷ በጽዮን ፡ ለአንተ ፡ ምስጋና ፡ ይገባል ÷
ለአንተም ፡ ጸሎት ፡ ይቀርባል ።
፪፤ ሥጋ ፡ ሁሉ ፡ ጸሎትን ፡ ወደምትሰማ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ይመጣል ።
፫፤ የዓመፃ ፡ ነገር ፡ በረታብን ፤
ኃጢአታችንንስ ፡ አንተ ፡ ይቅር ፡ ትላለህ ።
፬፤ አንተ ፡ የመረጥኸው ፡ በአደባባዮችህም ፡ ለማደር ፡ የተቀበልኸው ፡ ምስጉን ፡ ነው ፤
ከቤትህ ፡ በረከት ፡ እንጠግባለን ።
፭፤ ቤተ ፡ መቅደስህ ፡ ቅዱስ ፡ ነው ፡ በጽድቅም ፡ ድንቅ ፡ ነው ።
በምድር ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉና ፡ በሩቅ ፡ ባሕር ፡ ውስጥ ፡ ላሉ ፡ ተስፋቸው ፡ የሆንህ ÷
አምላካችንና ፡ መድኃኒታችን ፡ ሆይ ÷ ስማን ።
፮፤ በጉልበትህ ፡ ተራሮችን ፡ አጸናሃቸው ÷
በኃይልም ፡ ታጥቀሃል ።
፯፤ የባሕሩን ፡ ጥልቀት ፡
የሞገዱንም ፡ ጩኸት ፡ ታናውጣለህ ።
፰፤ ከተአምራትህ ፡ የተነሣ ፡ አሕዛብ ፡ ይደነግጣሉ ÷
በምድር ፡ ዳርቻም ፡ የሚኖሩ ፡ ይፈራሉ ፤
የጥዋትንና ፡ የማታን ፡ መውጫ ፡ ደስ ፡ ታሰኛቸዋለህ ።
፱፤ ምድርን ፡ ጐበኘሃት ፡ አጠጣሃትም ÷

ብልጥግናዋንም ፡ እጅግ ፡ አበዛህ ፤
የእግዚአብሔር ፡ ወንዝ ፡ ውኃን ፡ የተመላ ፡ ነው ፤
ምግባቸውን ፡ አዘጋጀህ ፤ እንዲሁ ፡ ታሰናዳለ
ህና ።
፲ ፡ ትልምዋን ፡ ታረካለህ ፥
በይዋንም ፡ ታስተካክላለህ ፤
በነጠብጣብ ፡ ታለሰልሳታለህ ፥
ቡቃያዋንም ፡ ትባርካለህ ።
፲፩ ፡ በቸርነትህ ፡ ዓመትን ፡ ታቀዳጃለህ ፥
ምድረ ፡ በዳውም ፡ ስብን ፡ ይጠግባል ።
፲፪ ፡ የምድረ ፡ በዳ ፡ ተራሮች ፡ ይረካሉ ፥
ኮረብቶችም ፡ በደስታ ፡ ይታጠቃሉ ።
፲፫ ፡ ማሰማርያዎች ፡ መንጎችን ፡ ለበሱ ፥
ሸለቆችም ፡ በእህል ፡ ተሸፈኑ ፤
በደስታ ፡ ይጮኻሉ ፡ ይዘምራሉም ።

## መዝሙር ፡ ፷፭ ። (፷፮)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የመንሣት ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩ ፡ በምድር ፡ ያላችሁ ፡ ሁሉ ፥ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ በሉ ፥
፪ ፡ ለስሙም ፡ ዘምሩ ፥ ለምስጋናውም ፡ ክብርን ፡ ስጡ ።
፫ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዲህ ፡ በሉት ፦ ሥራህ ፡ ግሩም ፡ ነው ፤
ኃይልህ ፡ ብዙ ፡ ሲሆን ፡ ጠላቶች ፡ ዋሹብህ ።
፬ ፡ በምድር ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ ለአንተ ፡ ይሰግዳሉ ፥
ለአንተም ፡ ይዘምራሉ ፥
ለስምህም ፡ ይዘምራሉ ።
፭ ፡ ኑ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ሥራ ፡ እዩ ፤
ከሰው ፡ ልጆች ፡ ይልቅ ፡ በምክር ፡ ግሩም ፡ ነው ።
፮ ፡ ባሕርን ፡ የብስ ፡ አደረጋት ፥
ወንዙንም ፡ በእግር ፡ ተሻገሩ ፤
በዚያ ፡ በእርሱ ፡ ደስ ፡ ይለናል ።
፯ ፡ በኃይሉ ፡ ለዘላለም ፡ ይገዛል ፤
ዓይኖቹ ፡ ወደ ፡ አሕዛብ ፡ ይመለከታሉ ፤
ዓመፀኞች ፡ ራሳቸውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አያድርጉ ።
፰ ፡ አሕዛብ ፡ ሆይ ፥ አምላካችንን ፡ ባርኩ ፥
የምስጋናውንም ፡ ድምፅ ፡ አሰሙ ።
፱ ፡ ነፍሴን ፡ በሕይወት ፡ ያኖራታል ፥
እግሮቼንም ፡ ለመናወጥ ፡ አልሰጠም ።
፲ ፡ አቤቱ ፥ ፈትነኸናልና ፥
ብርንም ፡ እንደሚያነጥሩት ፡ አንጥረኸናልና ።
፲፩ ፡ ወደ ፡ ወጥመድ ፡ አገባኸን ፥
በጀርባችንም ፡ መከራን ፡ አኖርህ ።
፲፪ ፡ በራሳችን ፡ ላይ ፡ ሰውን ፡ አስረገጥኸን ፤
በእሳትና ፡ በውኃ ፡ መካከል ፡ አለፍን ፥
ወደ ፡ ዕረፍትም ፡ አወጣኸን ።
፲፫፡፲፬ ፡ ከሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ እገባለሁ ፤
በመከራዬ ፡ ጊዜ ፡ በአፌ ፡ የተናገርሁትን ፡
ከንፈሮቼም ፡ ያሉትን ፡ ስእለቴን ፡
ለአንተ ፡ እፈጽማለሁ ።
፲፭ ፡ ከዕጣንና ፡ ከወጠጤዎች ፡ ጋር ፡
ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ፍሪዳን ፡ አቀርባለሁ ፤
ላሞችንና ፡ ፍየሎችን ፡ እሠዋልሃለሁ ።
፲፮ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩት ፡ ሁሉ ፥ ኑ ፥ ስሙኝ ፤
ለነፍሴ ፡ ያደረገላትን ፡ ልንገራችሁ ።
፲፯ ፡ በአፌ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ጮኽሁ ፥
በአንደበቴም ፡ አመሰገንሁት ።
፲፰ ፡ በልቤስ ፡ በደልን ፡ አይቼ ፡ ብሆን ፡
ጌታ ፡ አይሰማኝም ፡ ነበር ።
፲፱ ፡ ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰማኝ ፤
የልመናዬን ፡ ድምፅ ፡ አደመጠ ።
፳ ፡ ጸሎቴን ፡ ያልከለከለኝ ፡
ምሕረቱንም ፡ ከእኔ ፡ ያላራቀ ፡
እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ።

## መዝሙር ፡ ፷፮ ። (፷፯)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በበገናዎች ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይማረን ፡ ይባርከንም ፥
ፊቱንም ፡ በላያችን ፡ ያብራ ፤
፪ ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ ማዳንህን ፥
መንገድህንም ፡ በምድር ፡ እናውቅ ፡ ዘንድ ።
፫ ፡ አቤቱ ፥ አሕዛብ ፡ ያመስግኑህ ፥
አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ያመስግኑህ ።
፬ ፡ ለአሕዛብ ፡ በቅን ፡ ትፈርድላቸዋለህና ፥
አሕዛብንም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ትመራለህና ፡
አሕዛብ ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡ ሐሤትም ፡ ያድርጉ ።
፭ ፡ አቤቱ ፥ አሕዛብ ፡ ያመስግኑህ ፥
አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ያመስግኑህ ።
፮ ፡ ምድር ፡ ፍሬዋን ፡ ሰጠች ፤
እግዚአብሔር ፡ አምላካችንም ፡ ይባርከናል ።
፯ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይባርከናል ፥
የምድርም ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ ይፈሩታል ።

## መዝሙር ፡ ፷፯ ። (፷፰)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የዳዊት ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይነሣ ፥ ጠላቶቹም ፡ ይበተኑ ፥
የሚጠሉትም ፡ ከፊቱ ፡ ይሸሹ ።
፪ ፡ ጢስ ፡ እንደሚበንን ፡ እንዲሁ ፡ ይብነኑ ፤
ሰም ፡ በእሳት ፡ ፊት ፡ እንደሚቀልጥ ፥
እንዲሁ ፡ ኀጥኣን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይጥፉ ።
፫ ፡ ጻድቃንም ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፥
በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ሐሤት ፡ ያድርጉ ፥
በደስታም ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ።
፬ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተቀኙ ፡ ለስሙም ፡ ዘምሩ ፤
ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ለወጣም ፡ መንገድ ፡ አድርጉ ፤
ስሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ፥ በፊቱም ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፤
በፊቱም ፡ ይደነግጣሉ ።
፭ ፡ እግዚአብሔር ፡ በቅዱስ ፡ ቦታው ፡
ለድሀ ፡ አደጎች ፡ አባት ፥ ለባልቴቶችም ፡ ዳኛ ፡ ነው ።
፮ ፡ እግዚአብሔር ፡ ብቸኞችን ፡ በቤት ፡ ያሳድራቸዋል ፥
እስረኞችንም ፡ በኃይሉ ፡ ያወጣቸዋል ፤

ዓመፀኞች ፡ ግን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ይኖራሉ ።
፯፤ አቤቱ ÷ በሕዝብህ ፡ ፊት ፡ በወጣህ ፡ ጊዜ ÷
በምድረ ፡ በዳም ፡ ባለፍህ ፡ ጊዜ ÷
ምድር ፡ ተናወጠች ÷
፰፤ ከሲና ፡ አምላክ ፡ ፊት ÷ ከእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ፊት ፡
ሰማያትም ፡ አንጠበጠቡ ።
፱፤ አቤቱ ÷ የሞገስን ፡ ዝናብ ፡ ለርስትህ ፡ አዘነብህ ÷
በደከመም ፡ ጊዜ ፡ አንተ ፡ አጸናኸው ።
፲፤ እንስሶችህ ፡ በውስጡ ፡ አደሩ ፤
አቤቱ ÷ በቸርነትህ ፡ ለድሆች ፡ አዘጋጀህ ።
፲፩፤ እግዚአብሔር ፡ ቃሉን ፡ ሰጠ ፤
የሚያወሩት ፡ ብዙ ፡ ሠራዊት ፡ ናቸው ።
፲፪፤ የሠራዊት ፡ ነገሥታት ፡ ፈጥነው ፡ ይሸሻሉ ፤
በቤትም ፡ የምትኖር ፡ ምርኮን ፡ ተካፈለች ።
፲፫፤ በርስቶች ፡ መካከል ፡ ብታድሩ ÷
ክብር ፡ እንደ ፡ ተሠሩ ፡ እንደ ፡ ርግብ ፡ ክንፎች ÷
በቅጠልያ ፡ ወርቅም ፡ እንደ ፡ ተለበጡ ፡ ላባዎችዋ ፡ ትሆናላችሁ ።
፲፬፤ ሰማያዊ ፡ ንጉሥ ፡ በላይዋ ፡ ባዘዘ ፡ ጊዜ ÷
በሰልሞን ፡ ላይ ፡ በረዶ ፡ ዘነበ ።
፲፭፤ የእግዚአብሔር ፡ ተራራ ፡ የለመለመ ፡ ተራራ ፡ ነው ፤
የጸና ፡ ተራራና ፡ የለመለመ ፡ ተራራ ፡ ነው ።
፲፮፤ የጸኑ ፡ ተራራዎች ፡ ለምን ፡ ይነሣሉ ?
እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ተራራ ፡ ያድርበት ፡ ዘንድ ፡ ወደደው ፤
በእውነት ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ያድርበታል ።
፲፯፤ የእግዚአብሔር ፡ ሰረገላዎች ፡ የብዙ ፡ ብዙ ፡ ሺህ ፡ ናቸው ፤
ጌታ ፡ በመቅደሱ ፡ በሲና ፡ በመካከላቸው ፡ ነው ።
፲፰፤ ወደ ፡ ላይ ፡ ዓረግህ ÷ ምርኮን ፡ ማረክህ ÷
ስጦታንም ፡ ለሰዎች ፡ ሰጠህ ÷
ደግሞም ፡ ለዓመፀኞች ፡ በዚያ ፡ ያድሩ ፡ ዘንድ ።
፲፱፤ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ቡሩክ ፡ ነው ፤
እግዚአብሔር ፡ በየዕለቱ ፡ ቡሩክ ፡ ነው ፤
የመድኃኒታችን ፡ አምላክ ፡ ይረዳናል ።
፳፤ አምላካችንስ ፡ የደኅንነት ፡ አምላክ ፡ ነው ፤
ከሞት ፡ መውጣትም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ነው ።
፳፩፤ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ የጠላቶቹን ፡ ራስ ÷
በኃጢአት ፡ የሚሄድንም ፡ የጠጕሩን ፡ አናት ፡ ይቀጠቅጣል ።
፳፪፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ከባሳን ፡ አመጣቸዋለሁ ÷
ከባሕርም ፡ ጥልቅ ፡ እመልሳቸዋለሁ ÷
፳፫፤ እግሮችህ ፡ በደም ፡ ይረገጡ ፡ ዘንድ ÷
የውሾችህ ፡ ምላስ ፡ በጠላቶች ፡ ላይ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ።
፳፬፤ የአምላኬ ፡ የንጉሥ ፡ መንገድ ፡ በመቅደሱ ÷
አቤቱ ÷ መንገድህ ፡ ተገለጠ ።
፳፭፤ አለቆች ፡ ቀደሙ ÷ መዘምራንም ፡ ተከተሉ ፤
ከበሮን ፡ በሚመቱ ፡ በቈነጃጅት ፡ መካከል ።
፳፮፤ እግዚአብሔርን ፡ በጉባኤ ÷
ጌታችንንም ፡ በእስራኤል ፡ ምንጭ ፡ አመስግኑት ።
፳፯፤ ወጣቱ ፡ ብንያም ፡ በጕልበቱ ፡ በዚያ ፡ አለ ÷
ገዦቻቸው ፡ የይሁዳ ፡ አለቆች ÷
የዛብሎን ፡ አለቆችና ፡ የንፍታሌምም ፡ አለቆች ።
፳፰፤ አቤቱ ÷ ኃይልህን ፡ እዘዝ ፤
አቤቱ ÷ ይህንም ፡ ለእኛ ፡ የሠራኸውን ፡ አጽናው ።
፳፱፤ በኢየሩሳሌም ፡ ስላለው ፡ መቅደስህ ፡
ነገሥታት ፡ እጅ ፡ መንሻን ፡ ለአንተ ፡ ያመጣሉ ።
፴፤ በሸምበቆ ፡ ውስጥ ፡ ያሉትን ፡ አራዊት ÷
በአሕዛብ ፡ ውስጥ ፡ ያሉትን ፡ የበሬዎችንና ፡ የወይፈኖችን ፡ ጉባኤ ፡ ገሥጽ ÷
እንደ ፡ ብር ፡ የተፈተኑት ፡ አሕዛብ ፡ እንዳይዘጉ ፤
ሰልፍን ፡ የሚወድዱትን ፡ አሕዛብን ፡ በትናቸው ።
፴፩፤ መኳንንት ፡ ከግብጽ ፡ ይመጣሉ ፤
ኢትዮጵያ ፡ እጆችዋን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትዘረጋለች ።
፴፪፤ የምድር ፡ ነገሥታት ÷ ለእግዚአብሔር ፡ ተቀኙ ÷
ለጌታም ፡ ዘምሩ ።
፴፫፤ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ሰማየ ፡ ሰማያት ፡ ለወጣ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዘምሩ ፤
የኃይል ፡ ቃል ፡ የሆነ ፡ ቃሉን ÷ እነሆ ÷ ይሰጣል ።
፴፬፤ ለእግዚአብሔር ፡ ክብርን ፡ ስጡ ፤
ግርማው ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ÷
ኃይሉም ፡ በደመናት ፡ ላይ ፡ ነው ።
፴፭፤ እግዚአብሔር ፡ በቅዱሳኑ ፡ ላይ ፡ ድንቅ ፡ ነው ፤
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እርሱ ፡ ኃይልን ፡ ብርታትንም ፡ ለሕዝቡ ፡ ይሰጣል ፤
እግዚአብሔርም ፡ ይመስገን ።

## መዝሙር ፡ ፷፰ ። (፷፱)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በመለከቶች ፤
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ÷ ውኃ ፡ እስከ ፡ ነፍሴ ፡ ደርሶብኛልና ፡ አድነኝ ።
፪፤ በጥልቅ ፡ ረግረግ ፡ ጠለቅሁ ፡ መቋሚያም ፡ የለኝም ፤
ወደ ፡ ጥልቅ ፡ ባሕር ፡ ገባሁ ፡ ማዕበልም ፡ አሰጠመኝ ።
፫፤ በጩኸት ፡ ደከምሁ ፡ ጕሮሮዬም ፡ ሰለለ ፤
አምላኬን ፡ ስጠብቅ ፡ ዓይኖቼ ፡ ፈዘዙ ።
፬፤ በከንቱ ፡ የሚጠሉኝ ፡ ከራሴ ፡ ጠጕር ፡ በዙ ፤
በዓመፅ ፡ ያሚያሳድዱኝ ፡ ጠላቶቼ ፡ በረቱ ፤
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ያልቀማሁትን ፡ መለስሁ ።
፭፤ አቤቱ ÷ አንተ ፡ስንፍናዬን ፡ ታውቃለህ ÷
ኃጢአቴም ፡ ከአንተ ፡ አልተሰወረም ።
፮፤ አቤቱ ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ÷ ተስፋ ፡ የሚያደርጉህ ፡ በእኔ ፡ አይፈሩ ፤
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ የሚሹህ ፡ በእኔ ፡ አይነወሩ ።
፯፤ ስለ ፡ አንተ ፡ ስድብን ፡ ታግሻለሁና ÷
እፍረትም ፡ ፊቴን ፡ሸፍናለችና ።

፰፤ ለወንድሞቼ ፡ እንደ ፡ ሌላ ÷
ለእናቴ ፡ ልጆችም ፡ እንደ ፡ እንግዳ ፡ ሆንሁባቸው ።
፱፤ የቤትህ ፡ ቅንዓት ፡ በልታኛለችና ÷
የሚሰድቡህም ፡ ስድብ ፡ በላዬ ፡ ወድቆአልና ።
፲፤ ነፍሴን ፡ በጾም ፡ አስመረርሁአት ÷
ለስድብም ፡ ሆነብኝ ።
፲፩፤ ማቅ ፡ ለበስሁ ፡ ምሳሌም ፡ ሆንሁላቸው ።
፲፪፤ በደጅ ፡ የሚቀመጡ ፡ በእኔ ፡ ይጫወታሉ ፤
ወይን ፡ የሚጠጡ ፡ እኔን ፡ ይዘፍናሉ ።
፲፫፤ አቤቱ ÷ በመልካሙ ፡ ጊዜ ፡ ጸሎቴ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ነው ፤
አቤቱ ÷ በምሕረትህ ፡ ብዛት ፡ በማዳንህም ፡ እውነት ፡ አድምጠኝ ።
፲፬፤ እንዳይውጠኝ ፡ ከረግረግ ፡ አውጣኝ ፤
ከሚጠሉኝና ፡ ከጥልቅ ፡ ውኃ ፡ አስጥለኝ ።
፲፭፤ የውኃው ፡ ማዕበል ፡ አያስጥመኝ ÷ ጥልቁም ፡ አይዋጠኝ ÷
ጕድጓድም ፡ አፉን ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ አይዝጋ ።
፲፮፤ አቤቱ ÷ ምሕረትህ ፡ መልካም ፡ ናትና ፡ ስማኝ ፤
እንደ ፡ ርኅራኄህም ፡ ብዛት ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ተመልከት ፤
፲፯፤ ከባሪያህም ፡ ፊትህን ፡ አትሰውር ፤
ተጨንቄአለሁና ፡ ፈጥነህ ፡ አድምጠኝ ።
፲፰፤ ነፍሴን ፡ ተመልክተህ ፡ ተቤዣት ፤
ስለ ፡ ጠላቶቼም ፡ አድነኝ ።
፲፱፤ አንተ ፡ ስድቤን ፡ እፍረቴንም ፡ ነውሬንም ፡ ታውቃለህ ፤
የሚያስጨንቁኝ ፡ ሁሉ ፡ በፊትህ ፡ ናቸው ።
፳፤ ነፍሴ ፡ ስድብንና ፡ ኃሣርን ፡ ታገሠች ፤
አስተዛዛኝም ፡ ተመኘሁ ፡ አላገኘሁም ÷
የሚያጽናናኝም ፡ አጣሁ ።
፳፩፤ ለመብሌ ፡ ሐሞት ፡ ሰጡኝ ÷
ለጥማቴም ፡ ሆምጣጤ ፡ አጠጡኝ ።
፳፪፤ ማዕዳቸው ፡ በፊታቸው ፡
ለወጥመድ ፡ ለፍዳ ፡ ለዕንቅፋት ፡ ትሁንባቸው ፤
፳፫፤ ዓይኖቻቸው ፡ እንዳያዩ ፡ ይጨልሙ ÷
ጀርባቸውም ፡ ዘወትር ፡ ይጕበጥ ።
፳፬፤ መዓትህን ፡ በላያቸው ፡ አፍስስ ÷
የቍጣህ ፡ መቅሠፍትም ፡ ያግኛቸው ።
፳፭፤ ማደሪያቸው ፡ በረሃ ፡ ትሁን ÷
በድንኳኖቻቸውም ፡ የሚቀመጥ ፡ አይገኝ ፤
፳፮፤ አንተ ፡ የቀሠፍኸውን ፡ እነርሱ ፡ አሳድደዋልና ÷
በቍስሌም ፡ ላይ ፡ ጥዝጣዜ ፡ ጨመሩብኝ ።
፳፯፤ በኃጢአታቸው ፡ ላይ ፡ ኃጢአትን ፡ ጨምርባቸው ÷
በጽድቅህም ፡ አይግቡ ።
፳፰፤ ከሕያዋን ፡ መጽሐፍ ፡ ይደምሰሱ ÷
ከጻድቃንም ፡ ጋር ፡ አይጻፉ ።
፳፱፤ እኔ ፡ ችግረኛና ፡ ቍስለኛ ፡ ነኝ ፤
አቤቱ ÷ የፊትህ ፡ መድኃኒት ፡ ይቀበለኝ ።
፴፤ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ በዝማሬ ፡ አመሰግናለሁ ÷
በምስጋናም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርገዋለሁ ።
፴፩፤ ቀንድና ፡ ጥፍር ፡ ካበቀለ ፡ ከእምቦሳ ፡ ይልቅ ፡
እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ ያሰኘዋል ።
፴፪፤ ችግረኞች ፡ ያያሉ ፡ ደስም ፡ ይላቸዋል ፤
እግዚአብሔርን ፡ ፈልጉ ፡ ሕያዋንም ፡ ሁኑ ።
፴፫፤ እግዚአብሔር ፡ ችግረኞችን ፡ ሰምቶአልና ÷
እስረኞቹንም ፡ አልናቀምና ።
፴፬፤ ሰማይና ፡ ምድር ፡ ባሕርም ፡
በእርስዋም ፡ የሚንቀሳቀስ ፡ ሁሉ ፡ ያመሰግኑታል ።
፴፭፤ እግዚአብሔር ፡ ጽዮንን ፡ ያድናታልና ÷
የይሁዳንም ፡ ከተሞች ፡ ይሠራልና ፤
በዚያም ፡ ይቀመጣሉ ፡ ይወርሱአትማል ።
፴፮፤ የባሪያዎቹ ፡ ዘር ፡ ይኖሩባታል ÷
ስሙንም ፡ የሚወድዱ ፡ በዚያ ፡ ይቀመጣሉ ።

## መዝሙር ፡ ፷፱ ። (፸)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ ለመታሰቢያ ፤
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ÷ እኔን ፡ ለማዳን ፡ ተመልከት ፤
አቤቱ ÷ እኔን ፡ ለመርዳት ፡ ፍጠን ።
፪፤ ነፍሴን ፡ የሚሹአት ፡ ይፈሩ ፡ ይጐስቍሉም ÷
ክፉንም ፡ የሚመክሩብኝ ፡ ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ይመለሱ ፡ ይፈሩም ።
፫፤ እንኳ ፡ እንኳ ፡ የሚሉኝ ፡ አፍረው ፡ ወዲያው ፡ ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ይመለሱ ።
፬፤ የሚሹህ ፡ ሁሉ ፡ በአንተ ፡ ሐሤት ፡ ያድርጉ ፡ ደስም ፡ ይበላቸው ፤
ማዳንህን ፡ የሚወድዱ ፡ ሁልጊዜ ፡—እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡ ይበሉ ።
፭፤ እኔ ፡ ችግረኛና ፡ ምስኪን ፡ ነኝ ፤ አቤቱ ÷ እርዳኝ ፤
ረዳቴ ፡ ታዳጊዬም ፡ አንተ ፡ ነህ ፤ አቤቱ ÷ አትዘግይ ።

## መዝሙር ፡ ፸ ። (፸፩)

አስቀድመው ፡ ስለ ፡ ማረኩ ፡ ስለ ፡ አሚናዳብ ፡ ልጆች ፤
የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ÷ አንተን ፡ ታመንሁ ፤ ለዘላለም ፡ አልፈር ።
፪፤ በጽድቅህ ፡ አስጥለኝ ፡ ታደገኝም ፤
ጆሮህን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አዘንብል ፡ አድነኝም ።
፫፤ በጠንካራ ፡ በታ ፡ ታድነኝ ፡ ዘንድ ፡
አምላክና ፡ መሸሸጊያ ፡ ሁነኝ ፤
ኃይሌ ፡ መጠጊያዬ ፡ አንተ ፡ ነህና ።
፬፤ አምላኬ ÷ ከኃጢአተኛ ፡ እጅ ÷
ከዓመፀኛና ፡ ከግፈኛም ፡ እጅ ፡ አድነኝ ።
፭፤ አቤቱ ÷ አንተ ፡ ተስፋዬ ፡ ነህና ÷
እግዚአብሔር ፡ ሆይ ÷ ከታናሽነቴ ፡ ጀምረህ ፡ መታመኛዬ ፡ ነህና ።
፮፤ ከማሕፀን ፡ ጀምሮ ፡ በአንተ ፡ ተደገፍሁ ÷
ከእናቴም ፡ ሆድ ፡ ጀምሮ ፡ አንተ ፡ መሸሸጊያዬ ፡ ነህ ፤
ሁልጊዜም ፡ ዝማሬዬ ፡ ለአንተ ፡ ነው ።
፯፤ ለብዙዎች ፡ መደነቂያ ፡ ሆንሁ ፤

አንተ ፡ ግን ፡ ብርቱ ፡ መጠጊያዬ ፡ ነህ ።
፰፡ አፌን ፡ ምስጋና ፡ ምላ ፡
ሁልጊዜ ፡ ክብርህንና ፡ ግርማህን ፡ እዘምር ፡ ዘንድ ።
፱፡ በእርጅናዬ ፡ ዘመን ፡ አትጣለኝ ፥
ጕልበቴም ፡ በለቀ ፡ ጊዜ ፡ አትተወኝ ።
፲፡ ጠላቶቼ ፡ በላዬ ፡ ተናግረዋልና ፥
ነፍሴንም ፡ የሚሹአት ፡ በአንድነት ፡ ተማክረዋልና ፥ እንዲህም ፡ አሉ ፦
፲፩፡ እግዚአብሔር ፡ ትቶታል ፤
የሚያድነው ፡ የለምና ፡ ተከትላችሁ ፡ ያዙት ።
፲፪፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ ከእኔ ፡ አትራቅ ፤
አምላኬ ፡ ሆይ ፥ እኔን ፡ ለመርዳት ፡ ፍጠን ።
፲፫፡ ነፍሴን ፡ የሚቃወሙአት ፡ ይፈሩ ፡ ይጥፉም ፥
ጕዳቴንም ፡ የሚፈልጉ ፡ እፍረትንና ፡ ኀሣርን ፡ ይልበሱ ።
፲፬፡ እኔ ፡ ግን ፡ ሁልጊዜ ፡ ተስፋ ፡ አደርጋለሁ ፥
በምስጋናህም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እጨምራለሁ ።
፲፭፡ ሥራን ፡ አላውቅምና ፡
አፌ ፡ ጽድቅህን ፡ ሁልጊዜም ፡ ማዳንህን ፡ ይናገራል ።
፲፮፡ በእግዚአብሔር ፡ ኀይል ፡ እገባለሁ ፤
አቤቱ ፥ ጽድቅህን ፡ ብቻ ፡ አስባለሁ ።
፲፯፡ አምላኬ ፥ ከታናሽነቴ ፡ ጀምረህ ፡ አስተማርኸኝ ፤
እስከ ፡ ዛሬም ፡ ተአምራትህን ፡ እነግራለሁ ።
፲፰፡ እስክረጅም ፡ እስክሸመግልም ፡ ድረስ ፥
ለሚመጣ ፡ ትውልድም ፡ ሁሉ ፡ ክንድህን ፡
ኀይልህንም ፡ ጽድቅህንም ፡ እስክነግር ፡ ድረስ ፥
አቤቱ ፥ አትተወኝ ።
፲፱፡ አቤቱ ፥ እስከ ፡ አርያም ፡ ታላላቅ ፡ ነገሮችን ፡ አደረግህ ፤
አምላክ ፡ ሆይ ፥ እንደ ፡ አንተ ፡ ያለ ፡ ማን ፡ ነው ?
፳፡ ብዙ ፡ ጭንቀትንና ፡ መከራን ፡ አሳይተኸኛልና ፥
ተመለስህ ፡ ሕያውም ፡ አደረግኸኝ ፤
ከምድር ፡ ጥልቅም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ አወጣኸኝ ።
፳፩፡ ጽድቅህንም ፡ አብዛው ፥
ተመልሰህም ፡ ደስ ፡ አሰኘኝ ፥
ከጥልቅም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ አወጣኸኝ ።
፳፪፡ እኔም ፡ በበገና ፡ ስለ ፡ እውነትህ ፡ አመሰግንሃለሁ ፤
የእስራኤል ፡ ቅዱስ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ በመሰንቆ ፡ እዘምርልሃለሁ ።
፳፫፡ ዝማሬን ፡ በቀረብሁልህ ፡ ጊዜ ፡ ከንፈሮቼ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፥
አንተ ፡ ያዳንሃትም ፡ ነፍሴ ።
፳፬፡ ጕዳቴን ፡ የሚሹ ፡ በፈሩና ፡ በተነወሩ ፡ ጊዜ ፡
አንደበቴ ፡ ደግሞ ፡ ሁልጊዜ ፡ ጽድቅህን ፡ ይናገራል ።

## መዝሙር ፡ ፸፩ ። (፸፪)

ስለ ፡ ሰሎሞን ።

፩፡ አቤቱ ፥ ፍርድህን ፡ ለንጉሥ ፡ ስጥ ፥
ጽድቅህንም ፡ ለንጉሥ ፡ ልጅ ፥
፪፡ ሕዝብህን ፡ በጽድቅ ፥
ችግረኞችህንም ፡ በፍርድ ፡ ይዳኝ ፡ ዘንድ ።
፫፡ ተራሮችና ፡ ኰረብቶች ፡ ለሕዝብህ ፡ ሰላምን ፡ ይቀበሉ ።
፬፡ ለችግረኞች ፡ ሕዝብ ፡ በጽድቅ ፡ ትፈርዳለህ ፥
የድሆችንም ፡ ልጆች ፡ ታድናለህ ፤
ክፉውንም ፡ ታዋርደዋለህ ።
፭፡ ፀሐይ ፡ በሚኖርበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፥
በጨረቃም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ይኖራል ።
፮፡ እንደ ፡ ዝናብ ፡ በታጨደ ፡ መስክ ፡ ላይ ፥
በምድርም ፡ ላይ ፡ እንደሚንጠባጠብ ፡ ጠብታ ፡ ይወርዳል ።
፯፡ በዘመኑም ፡ ጽድቅ ፡ ያብባል ፥
ጨረቃም ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፡ ሰላም ፡ ብዙ ፡ ነው ።
፰፡ ከባሕር ፡ እስከ ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፥
ከወንዝም ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ይገዛል ።
፱፡ በፊቱም ፡ ኢትዮጵያ ፡ ይሰግዳሉ ፥
ጠላቶቹም ፡ አፈር ፡ ይልሳሉ ።
፲፡ የተርሴስና ፡ የደሴቶች ፡ ነገሥታት ፡ ስጦታን ፡ ያመጣሉ ፤
የዓረብና ፡ የሳባ ፡ ነገሥታት ፡ እጅ ፡ መንሻን ፡ ያቀርባሉ ።
፲፩፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ ይሰግዱለታል ፥
አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ ይገዙለታል ።
፲፪፡ ችግረኛውን ፡ ከቀማኛው ፡ እጅ ፥
ረዳት ፡ የሌለውንም ፡ ምስኪን ፡ ያድነዋልና ።
፲፫፡ ለችግረኛና ፡ ለምስኪን ፡ ይራራል ፥
የችግረኞችንም ፡ ነፍስ ፡ ያድናል ።
፲፬፡ ከግፍና ፡ ከጭንቀት ፡ ነፍሳቸውን ፡ ያድናል ፤
ስማቸው ፡ በፊቱ ፡ ክቡር ፡ ነው ።
፲፭፡ እርሱ ፡ ይኖራል ፡ ከዓረብም ፡ ወርቅ ፡ ይሰጡታል ፤
ሁልጊዜም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ይጸልያሉ ፥
ዘወትርም ፡ ይባርኩታል ።
፲፮፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡ በተራሮች ፡ ላይ ፡ መጠጊያ ፡ ይሆናል ፤
ፍሬውም ፡ ከሊባኖስ ፡ ይልቅ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ፤
እንደ ፡ ምድር ፡ ሣር ፡ በከተማ ፡ ይበቅላል ።
፲፯፡ ስሙ ፡ ለዘላለም ፡ ቡሩክ ፡ ይሆናል ፥
ከፀሐይም ፡ አስቀድሞ ፡ ስሙ ፡ ይኖራል ፤
የምድር ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ ይባረካሉ ፥
አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ያመሰግኑታል ።
፲፰፡ ብቻውን ፡ ተአምራትን ፡ የሚያደርግ ፡
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ።
፲፱፡ የምስጋናው ፡ ስም ፡ ለዓለምና ፡ ለዘላለም ፡ ይባረክ ፤
ምስጋናውም ፡ ምድርን ፡ ሁሉ ፡ ይምላ ።
ይሁን ፤ ይሁን ።
፳፡ የእሴይ ፡ ልጅ ፡ የዳዊት ፡ መዝሙር ፡ ተፈጸመ ።

## መዝሙር ፡ ፸፪ ። (፸፫)

የአሳፍ ፡ መዝሙር ።

፩፡ ልባቸው ፡ ለቀና ፡ ለእስራኤል ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዴት ፡ ቸር ፡ ነው ።

፪፤ እኔ ፡ ግን ፡ እግሮቼ ፡ ሊሰናከሉ ፥
አረማመዴም ፡ ሊወድቅ ፡ ትንሽ ፡ ቀረ ፡፡
፫፤ የኃጢአተኞችን ፡ ሰላም ፡ አይቼ ፡
በዓመፀኞች ፡ ቀንቼ ፡ ነበርና ፡፡
፬፤ ለሞታቸው ፡ መጣጣር ፡ የለውምና ፤
ኃይላቸውም ፡ ጠንካራ ፡ ነውና ፡፡
፭፤ እንደ ፡ ሰው ፡ በድካም ፡ አልሆኑም ፥
ከሰው ፡ ጋርም ፡ አልተገረፉም ፡፡
፮፤ ስለዚህ ፡ ትዕቢት ፡ ያዛቸው ፤
ኃጢአትንና ፡ በደልን ፡ ተጐናጸፉአት ፡፡
፯፤ ዓይናቸው ፡ ስብ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ወጣ ፤
ልባቸውም ፡ ከምኞታቸው ፡ ይልቅ ፡ አገኘ ፡፡
፰፤ አሰበው ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ተናገሩ ፤
ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብለውም ፡ በዓመፃ ፡ ተናገሩ ፡፡
፱፤ አፋቸውን ፡ በሰማይ ፡ አኖሩ ፥
አንደበታቸውም ፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡ ተመላለሰ ፡፡
፲፤ ስለዚህ ፡ ሕዝቤ ፡ ወደዚህ ፡ ይመለሳሉ ፤
ፍጹም ፡ ጊዜም ፡ በላያቸው ፡ ይገኛል ፤
፲፩፤ እግዚአብሔር ፡ እንዴት ፡ ያውቃል ?
በልዑልስ ፡ ዘንድ ፡ በውኑ ፡ እውቀት ፡ አለ ?
ይላሉ ፡፡
፲፪፤ እነሆ ፥ እነዚህ ፡ ኃጢአተኞች ፡ ይደሰታሉ ፥
ሁልጊዜም ፡ በለጠግነታቸውን ፡ ያበዛሉ ፡፡
፲፫፤ እንዲህም ፡ አልሁ ፡— በውኑ ፡ ልቤን ፡ በከንቱ ፡ አጸደቅሁ ፥
እጆቼንም ፡ በንጽሕና ፡ በከንቱ ፡ አጠብሁ ፡፡
፲፬፤ ሁልጊዜም ፡ የተገረፍሁ ፡ ሆንሁ ፥
መሰደቤም ፡ በማለዳ ፡ ነው ፡፡
፲፭፤ እንደዚህ ፡ ብዬ ፡ ብናገር ፡ ኖሮ ፥
እነሆ ፥ የልጆችህን ፡ ትውልድ ፡ በበደልሁ ፡ ነበር ፡፡
፲፮፤ አውቅም ፡ ዘንድ ፡ አሰብሁ ፥
ይህ ፡ ግን ፡ በፊቴ ፡ ችግር ፡ ነበረ ፡፡
፲፯፤ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ እስከገባ ፡ ድረስ ፥
ፍጻሜአቸውንም ፡ እስከስተውል ፡ ድረስ ፡፡
፲፰፤ በድጥ ፡ ስፍራ ፡ አስቀመጥኻቸው ፥
ወደ ፡ ጥፋትም ፡ ጣልኻቸው ፡፡
፲፱፤ እንዴት ፡ ለጥፋት ፡ ሆኑ !
በድንገት ፡ አለቁ ፡ ስለ ፡ ኃጢአታቸውም ፡ ጠፉ ፡፡
፳፤ ከሕልም ፡ እንደሚነቃ ፥
አቤቱ ፥ ስትነቃ ፡ ምልክታቸውን ፡ ታስነውራለህ ፡፡
፳፩፤ ልቤ ፡ ነድዶአልና ፥ ኵላሊቴም ፡ ቀልጦአልና ፤
፳፪፤ እኔ ፡ የተናቅሁ ፡ ነኝ ፡ አላወቅሁምም ፥
በአንተ ፡ ዘንድም ፡ እንደ ፡ እንስሳ ፡ ሆንሁ ፡፡
፳፫፤ እኔ ፡ ግን ፡ ዘወትር ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነኝ ፥
ቀኝ ፡ እጄንም ፡ ያዝኸኝ ፡፡
፳፬፤ በአንተ ፡ ምክር ፡ መራኸኝ ፤
ከክብር ፡ ጋር ፡ ተቀበልኸኝ ፡፡
፳፭፤ በሰማይ ፡ ያለኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
በምድርስ ፡ ውስጥ ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ ምን ፡ እሻለሁ ?
፳፮፤ የልቤ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ ልቤና ፡ ሥጋዬ ፡ አለቀ ፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ እድል ፡ ፈንታዬ ፡ ነው ፡፡
፳፯፤ እነሆ ፥ ከአንተ ፡ የሚርቁ ፡ ይጠፋሉና ፤
ከአንተ ፡ ርቀው ፡ የሚያመነዝሩትንም ፡ ሁሉ ፡ አጠፋኻቸው ፡፡
፳፰፤ ለእኔ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መቅረብ ፡ ይሻለኛል ፤
መታመኛዬም ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ፡
በጽዮን ፡ ልጅ ፡ በሮች ፡ ምስጋናህን ፡ ሁሉ ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡፡

## መዝሙር ፡ ፸፫ ፡፡ (፸፬)

የአሳፍ ፡ ትምህርት ፡፡

፩፤ አቤቱ ፥ ስለ ፡ ምን ፡ ለዘወትር ፡ ጣልኸን ?
በማሰማርያህ ፡ በጎች ፡ ላይስ ፡ ቍጣህን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ተቈጣህ ?
፪፤ አስቀድመህ ፡ የፈጠርሃትን ፡ ማኅበርህን ፥
የተቤዠሃትንም ፡ የርስትህን ፡ በትር ፥
በእርስዋ ፡ ያደርህባትን ፡ የጽዮንን ፡ ተራራ ፡ አስብ ፡፡
፫፤ ጠላት ፡ በቅዱሳንህ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ክፉ ፡ መጠን ፥
ሁልጊዜ ፡ በትዕቢታቸው ፡ ላይ ፡ እጅህን ፡ አንሣ ፡፡
፬፤ ጠላቶችህ ፡ በበዓልህ ፡ መካከል ፡ ተመኩ ፤
የማያውቁትንም ፡ ምልክት ፡ ምልክታቸው ፡ አደረጉ ፡፡
፭፤ እንደ ፡ ላይኛው ፡ መግቢያ ፡ ውስጥ ፥
በዱር ፡ እንዳሉም ፡ እንጨቶች ፥
በመጥረቢያ ፡ በሮችዋን ፡ ሰበሩ ፡፡
፮፤ እንዲሁ ፡ በመጥረቢያና ፡ በመዶሻ ፡ ሰበሩአት ፡፡
፯፤ መቅደስህን ፡ በእሳት ፡ አቃጠሉ ፤
የስምህንም ፡ ማደሪያ ፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡ አረከሱ ፡፡
፰፤ አንድ ፡ ሆነው ፡ በልባቸው ፡ በየሕዝባቸው ፡— ኑ ፥ የእግዚአብሔርን ፡ በዓሎች ፡ ከምድር ፡ እንሻር ፡ አሉ ፡፡
፱፤ ምልክታችንን ፡ አናይም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህም ፡ ነቢይ ፡ የለም ፤
እስከ ፡ መቼ ፡ እንዲኖር ፡ የሚያውቅ ፡ በኛ ፡ ዘንድ ፡ የለም ፡፡
፲፤ አቤቱ ፥ ጠላት ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ይሳደባል ?
ስምህን ፡ ጠላት ፡ ሁልጊዜ ፡ ያቃልላል ?
፲፩፤ ቀኝህን ፡ በብብትህ ፡ መካከል ፥
እጅህንም ፡ ፈጽመህ ፡ ለምን ፡ ትመልሳለህ ?
፲፪፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ከዓለም ፡ አስቀድሞ ፡ ንጉሥ ፡ ነው ፥
በምድርም ፡ መካከል ፡ መድኃኒትን ፡ አደረገ ፡፡
፲፫፤ አንተ ፡ ባሕርን ፡ በኃይልህ ፡ አጸናሃት ፤
አንተ ፡ የእባቦችን ፡ ራስ ፡ በውኃ ፡ ውስጥ ፡ ሰበርህ ፡፡
፲፬፤ አንተም ፡ የዘንዶውን ፡ ራሶች ፡ ቀጠቀጥህ ፤
ለኢትዮጵያ ፡ ሰዎችም ፡ ምግባቸውን ፡ ሰጠሃቸው ፡፡
፲፭፤ አንተ ፡ ምንጮቹንና ፡ ፈሳሾቹን ፡ ሰነጠቅህ ፤
አንተ ፡ ሁልጊዜ ፡ የሚፈስሱትን ፡ ወንዞች ፡ አደረቅህ ፡፡

፲፮፤ ቀኑ ፡ የአንተ ፡ ነው ፡ ሌሊቱም ፡ የአንተ ፡ ነው ፤
አንተ ፡ ፀሓዩንና ፡ ጨረቃውን ፡ አዘጋጀህ ።
፲፯፤ አንተ ፡ የምድርን ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ ሠራህ ፤
በጋንም ፡ ክረምትንም ፡ አንተ ፡ አደረግህ ።
፲፰፤ ይህን ፡ ፍጥረትህን ፡ አስብ ።
ጠላት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተላገደ ፥
ሰነፍ ፡ ሕዝብም ፡ ስሙን ፡ አስቈጣ ።
፲፱፤ የምትገዛልህን ፡ ነፍስ ፡ ለአራዊት ፡ አትስጣት ፤
የችግረኞችህን ፡ ነፍስ ፡ ለዘወትር ፡ አትርሳ ።
፳፤ ወደ ፡ ኪዳንህ ፡ ተመልከት ፥
የምድር ፡ የጨለማ ፡ ስፍራዎች ፡ በኀጥአን ፡
ቤቶች ፡ ተሞልተዋልና ።
፳፩፤ ችግረኛ ፡ አፍሮ ፡ አይመለስ ፤
ችግረኛና ፡ ምስኪን ፡ ስምህን ፡ ያመሰግናሉ ።
፳፪፤ አቤቱ ፥ ተነሥ ፡ በቀልህንም ፡ ተበቀል ፤
ሰነፎች ፡ ሁልጊዜ ፡ የተላገዱህን ፡ አስብ ።
፳፫፤ የባሪያዎችህን ፡ ቃል ፡ አትርሳ ፤
የጠላቶችህ ፡ ኵራት ፡ ሁልጊዜ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡
ይወጣል ።

## መዝሙር ፡ ፸፬ ። (፸፭)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ አታጥፋ ። የአሳፍ ፡ የምስጋና ፡
መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ፥ እናመሰግንሃለን ፤
እናመሰግንሃለን ፡ ስምህንም ፡ እንጠራለን ፤
ተአምራትህን ፡ ሁሉ ፡ እናገራለሁ ።
፪፤ ጊዜውን ፡ ስቀበል ፡ እኔ ፡ በቅን ፡ እፈርዳለሁ ።
፫፤ ምድርና ፡ በእርስዋ ፡ ውስጥ ፡ የሚኖሩት ፡ ሁሉ ፡
ቀለጡ ፥
እኔም ፡ ምሰሶችዋን ፡ አጠናሁ ።
፬፤ ዓመፀኞችን ፦ አትበድሉ ፡ አልኋቸው ፥
ኃጢአተኞችንም ፦ ቀንዳችሁን ፡ አታንሡ ፤
፭፤ ቀንዳችሁን ፡ እስከ ፡ ላይ ፡ አታንሡ ፥
በእግዚአብሔርም ፡ ላይ ፡ ዓመፅን ፡ አትናገሩ ።
፮፤ ክብር ፡ ከምሥራቅ ፡ ወይም ፡ ከምዕራብ ፡ ወይም ፡
ከምድረ ፡ በዳ ፡ የለምና ፤
፯፤ እግዚአብሔር ፡ ፈራጅ ፡ ነውና ፡
ይህን ፡ ያዋርዳል ፡ ይህንም ፡ ያከብራል ።
፰፤ ጽዋ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ነውና ፤
ያልተቀላቀለ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ሞላበት ፤
ከዚህ ፡ ወደዚያ ፡ አገላበጠው ፥
ነገር ፡ ግን ፡ አተላው ፡ አልፈሰሰም ፤
የምድር ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሁሉ ፡ ይጠጡታል ።
፱፤ እኔ ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፥
ለያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ ዝማሬን ፡ አቀርባለሁ ።
፲፤ የኀጥአንን ፡ ቀንዶች ፡ ሁሉ ፡ እሰብራለሁ ፤
የጻድቃን ፡ ቀንዶች ፡ ግን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላሉ ።

## መዝሙር ፡ ፸፭ ። (፸፮)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በበገናዎች ፤ ስለ ፡ አሦራውያን ፤
የአሳፍ ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ በይሁዳ ፡ ታወቀ ፥
ስሙም ፡ በእስራኤል ፡ ታላቅ ፡ ነው ።
፪፤ ስፍራው ፡ በሳሌም ፥ ማደሪያውም ፡ በጽ
ዮን ፡ ነው ፤
፫፤ በዚያም ፡ የቀስትን ፡ ኃይል ፥
ጋሻን ፡ ሰይፍን ፡ ሰልፍንም ፡ ሰበረ ፤
በዚያም ፡ ቀንዶችን ፡ ሰበረ ።
፬፤ አንተ ፡ በዘላለም ፡ ተራሮች ፡ ሆንህ ፡ በድንቅ ፡
ታበራለህ ።
፭፤ ልበ ፡ ሰነፎች ፡ ሁሉ ፡ ደነገጡ ፥
እንቅልፋቸውንም ፡ አንቀላፉ ፤
ባለጠጎች ፡ ሁሉ ፡ በእነርሱ ፡ እጅ ፡ ምንም ፡ አላ
ገኙም ።
፮፤ የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ ከተግሣጽህ ፡ የተነሣ ፡
ፈረሰኞች ፡ ሁሉ ፡ አንቀላፉ ።
፯፤ አንተ ፡ ግን ፥ አንተ ፡ ግሩም ፡ ነህ ፤
ቍጣህን ፡ ማን ፡ ይቃወማል ?
፰፤ ፍርድን ፡ ከሰማይ ፡ አሰማህ ፤
ምድር ፡ ፈራች ፡ ዝምም ፡ አለች ፥
፱፤ ልበ ፡ የዋሃን ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡
እግዚአብሔር ፡ ለፍርድ ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ።
፲፤ ሰው ፡ በፈቃዱ ፡ ያመሰግንሃልና ፥
ከሕሊናቸው ፡ ትርፍም ፡ በዓልህን ፡ ያደርጋሉ ።
፲፩፤ ለአምላካችን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስእለትን ፡
ክፈሉ ፤
በዙሪያው ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ መንሻን ፡ ለሚ
ያስፈራው ፡ ያገብሉ ።
፲፪፤ የመኳንንትን ፡ ነፍስ ፡ ያወጣል ፤
በምድርም ፡ ነገሥታት ፡ ዘንድ ፡ ያስፈራል ።

## መዝሙር ፡ ፸፮ ። (፸፯)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ ስለ ፡ ኤዶታም ፤
የአሳፍ ፡ መዝሙር ።

፩፤ በቃሌ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኽሁ ፥
ቃሌም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ፥ እርሱም ፡
አደመጠኝ ።
፪፤ በመከራዬ ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈለግሁት ፤
እጆቼ ፡ በሌሊት ፡ በፊቱ ፡ ናቸው ፥ አላረፍ
ሁምም ፥
ነፍሴም ፡ መጽናናትን ፡ አልቻለችም ።
፫፤ እግዚአብሔርን ፡ አሰብሁት ፡ ደስ ፡ አለኝም ፤
ተናገርሁ ፥ ነፍሴም ፡ ፈዘዘች ።
፬፤ ዓይኖቼ ፡ እንዲተጉ ፡ ያዝሃቸው ፤
ደነገጥሁ ፡ አልተናገርሁም ።
፭፤ የዱሮውን ፡ ዘመን ፡ አሰብሁ ፤
የዘላለሙን ፡ ዓመታት ፡ አሰብሁ ፤ አጠናጠን
ሁም ፤
፮፤ በሌሊት ፡ ከልቤ ፡ ጋር ፡ ተጫወትሁ ፥
ነፍሴንም ፡ አነቃቃኋት ።
፯፤ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ይጥላልን ?
እንግዲህስ ፡ ቸርነቱን ፡ አይጨምርምን ?
፰፤ ለዘላለምስ ፡ ምሕረቱ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ተቈረጠ
ችን ?
የተናገረውስ ፡ ቃል ፡ አልቆአልን ?
፱፤ እግዚአብሔርስ ፡ ሞገሱን ፡ ረሳን ?
በቍጣውስ ፡ ምሕረቱን ፡ ዘጋውን ?
፲፤ ይህ ፡ ድካሜ ፡ ነው ፡ አልሁ ፥

የልዑል ፡ ቀኝ ፡ እንደ ፡ ተለወጠ ።
፲፩ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ አስታወስሁ ፤
የቀደመውን ፡ ተአምራትህን ፡ አስታውሳለሁና ፤
፲፪ በምግባርህም ፡ ሁሉ ፡ እናገራለሁ ፥
በሥራህም ፡ እጫወታለሁ ።
፲፫ አቤቱ ፥ መንገድህ ፡ በመቅደስ ፡ ውስጥ ፡ ነው ፤
እንደ ፡ አምላካችን ፡ ያለ ፡ ታላቅ ፡ አምላክ ፡ ማን ፡ ነው ?
፲፬ ተአምራትን ፡ የምታደርግ ፡ አምላክ ፡ አንተ ፡ ነህ ፤
ለሕዝብህ ፡ ኃይልህን ፡ አስታወቅሃቸው ።
፲፭ የያዕቆብንና ፡ የዮሴፍን ፡ ልጆች ፥
ሕዝብህን ፡ በክንድህ ፡ አዳንሃቸው ።
፲፮ አቤቱ ፥ ውኆች ፡ አዩህ ፥
ውኆችም ፡ አይተውህ ፡ ፈሩ ፤
ጥልቆች ፡ ተነዋወጡ ፥ ውኆችም ፡ ጮኹ ።
፲፯ ደመኖች ፡ ድምፅን ፡ ሰጡ ፥
ፍላጾችህም ፡ ወጡ ።
፲፰ የነጐድጓድህ ፡ ድምፅ ፡ በዐውሎ ፡ ነበረ ፤
መብረቆች ፡ ለዓለም ፡ አበሩ ፤
ምድር ፡ ተናወጠች ፡ ተንቀጠቀጠችም ።
፲፱ መንገድህ ፡ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ ነው ፥
ፍለጋህም ፡ በብዙ ፡ ውኆች ፡ ነው ፥
አረማመድህም ፡ አልታወቀም ።
፳ በሙሴና ፡ በአሮን ፡ እጅ ፡
ሕዝብህን ፡ እንደ ፡ በጎች ፡ መራሃቸው ።

## መዝሙር ፡ ፸፯ ። (፸፰)

የአሳፍ ፡ ትምህርት ።

፩ ሕዝቤ ፡ ሆይ ፥ ሕጌን ፡ አድምጡ ፤
ጆሮአችሁንም ፡ ወደ ፡ አፌ ፡ ቃል ፡ አዘንብሉ ።
፪ አፌን ፡ በምሳሌ ፡ እከፍታለሁ ፤
ከቀድሞ ፡ ጀምሮ ፡ ያለውንም ፡ ተምሳሊት ፡ እናገራለሁ ።
፫ የሰማነውንና ፡ ያወቅነውን ፥
አባቶቻችንም ፡ የነገሩንን ፥
ለሚመጣ ፡ ትውልድ ፡ ከልጆቻቸው ፡ አልሰወሩም ።
፬ የእግዚአብሔርን ፡ ምስጋናና ፡ ኃይሉን ፥
ያደረገውንም ፡ ተአምራት ፡ ተናገሩ ።
፭ ለልጆቻቸው ፡ ያስታውቅ ፡ ዘንድ ፥
ለአባቶቻችን ፡ ያዘዘውን ፡ ምስክር ፡
በያዕቆብ ፡ አቆመ ፥
በእስራኤልም ፡ ሕግን ፡ ሠራ ፤
፮ የሚመጣ ፡ ትውልድ ፡ የሚወለዱም ፡ ልጆች ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፥
ተነሥተው ፡ ለልጆቻቸው ፡ ይነግራሉ ፤
፯ ተስፋቸውን ፡ በእግዚአብሔር ፡ እንዲያደርጉ ፥
የእግዚአብሔርንም ፡ ሥራ ፡ እንዳይረሱ ፥
ትእዛዙንም ፡ እንዲጠብቁ ፤
፰ እንደ ፡ አባቶቻቸው ፡ እንዳይሆኑ ፥
ጠማማና ፡ የምታስመርር ፡ ትውልድ ፥
ልብዋን ፡ ያላቀናች ፡ ትውልድ ፥
ነፍስዋ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ያልታመነች ።
፱ የኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ ለሰልፍ ፡ ታጥቀው ፡ ቀስትንም ፡ ገትረው ፡
በሰልፍ ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ተመለሱ ።
፲ የእግዚአብሔርን ፡ ኪዳን ፡ አልጠበቁም ፥
በሕጉም ፡ ለመመላለስ ፡ እንቢ ፡ አሉ ፤
፲፩ መልካም ፡ ሥራውንና ፡ ያሳያቸውን ፡ ተአምራቱን ፡ ረሱ ፥
፲፪ በግብጽ ፡ አገርና ፡ በጣኔዎስ ፡ በረሃ ፡
በአባቶቻቸው ፡ ፊት ፡ የሠራውን ፡ ተአምራት ።
፲፫ ባሕርን ፡ ከፍሎ ፡ አሳለፋቸው ፤
ውኆችን ፡ እንደ ፡ ክምር ፡ አቆመ ።
፲፬ ቀን ፡ በደመና ፡ መራቸው ፥
ሌሊቱንም ፡ ሁሉ ፡ በእሳት ፡ ብርሃን ።
፲፭ ዓለቱን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ሰነጠቀ ፤
ከጥልቅ ፡ እንደሚገኝ ፡ ያህል ፡ በብዙ ፡ አጠጣቸው ።
፲፮ ውኃን ፡ ከጭንጫ ፡ አወጣ ፥
ውኃንም ፡ እንደ ፡ ወንዞች ፡ አፈሰሰ ።
፲፯ ነገር ፡ ግን ፡ ይበድሉት ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ደገሙ ፥
ልዑልንም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ አስቈጡት ።
፲፰ ለነፍሳቸው ፡ መብልን ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ፥
እግዚአብሔርን ፡ በልባቸው ፡ ፈተኑት ።
፲፱ እግዚአብሔርን ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ አሙት ፡—
እግዚአብሔር ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ማዕድን ፡ ያሰናዳ ፡ ዘንድ ፡ ይችላልን ?
፳ ዓለቱን ፡ መታ ፤ ውኆችም ፡ ወጡ ፥ ወንዞችም ፡ ጐረፉ ፤
እንጀራን ፡ መስጠትስ ፡ ይችላልን ?
ለሕዝቡስ ፡ ማዕድን ፡ ያዘጋጃልን ?
፳፩ እግዚአብሔርም ፡ ይህን ፡ ሰምቶ ፡ ተቈጣ ፤
በያዕቆብም ፡ ላይ ፡ እሳት ፡ ነደደ ፥
መዓትም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ መጣ ፤
፳፪ በእግዚአብሔር ፡ አላመኑምና ፥
በመድኃኒቱም ፡ አልተማመኑምና ።
፳፫ ደመናውንም ፡ ከላይ ፡ አዘዘ ፥
የሰማይንም ፡ ደጆች ፡ ከፈተ ፤
፳፬ ይበሉም ፡ ዘንድ ፡ መናን ፡ አዘነበላቸው ፥
የሰማይንም ፡ እንጀራ ፡ ሰጣቸው ።
፳፭ የመላእክትንም ፡ እንጀራ ፡ ሰው ፡ በላ ፤
ስንቅንም ፡ እስኪተርፋቸው ፡ ላከላቸው ።
፳፮ ከሰማይ ፡ የምሥራቅን ፡ ነፋስ ፡ አስነሣ ፥
በኃይሉም ፡ የደቡብን ፡ ነፋስ ፡ አመጣ ፤
፳፯ ሥጋን ፡ እንደ ፡ አፈር ፥
የሚበርሩትንም ፡ ወፎች ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ አሸዋ ፡ አዘነበላቸው ፤
፳፰ በሰፈራቸው ፡ መካከል ፥
በድንኳናቸውም ፡ ዙሪያ ፡ ወደቀ ።
፳፱ በሉ ፡ እጅግም ፡ ጠገቡ ፤
ምኞታቸውንም ፡ ሰጣቸው ።
፴ ከወደዱትም ፡ አላሳጣቸውም ፤
መብላቸውም ፡ ገና ፡ በአፋቸው ፡ ሳለ ፥
፴፩ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በላያቸው ፡ መጣ ፥
ከእነርሱም ፡ ከፍ ፡ ያሉቱን ፡ ገደለ ፥

የእስራኤልንም ፡ ምርጦች ፡ አሰናከለ ።
፴፪ ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ገና ፡ በደሉ ፥
ተአምራቱንም ፡ አላመኑም ፤
፴፫ ቀኖቻቸውም ፡ በከንቱ ፡ አለቁ ፥
ዓመቶቻቸውም ፡ በችኰላ ።
፴፬ በገደላቸውም ፡ ጊዜ ፡ ወዲያው ፡ ፈለጉት ፤
ተመለሱ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ገሠገሡ ፤
፴፭ ረዳታቸውም ፡ እግዚአብሔር ፥
መድኀኒታቸውም ፡ ልዑል ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ አሰቡ ።
፴፮ በአፋቸው ፡ ብቻ ፡ ወደዱት ፤
በአንደበታቸውም ፡ ዋሹበት ፤
፴፯ ልባቸውም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አልቀናም ፥
በቃል ፡ ኪዳኑም ፡ አልተማመኑትም ።
፴፰ እርሱ ፡ ግን ፡ መሐሪ ፡ ነው ፥
ኃጢአታቸውንም ፡ ይቅር ፡ አላቸው ፥ አላጠፋ
ቸውምም ፤
ቍጣውንም ፡ መመለስ ፡ አበዛ ፥
መዓቱንም ፡ ሁሉ ፡ አላቃጠለም ።
፴፱ ወጥቶ ፡ የማይመለስ ፡ መንፈስ ፥
ሥጋም ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ አሰበ ።
፵ በምድረ ፡ በዳ ፡ ምን ፡ ያህል ፡ አስቈጡት ፥
በበረሃም ፡ አሳዘኑት ።
፵፩ ተመለሱ ፥ እግዚአብሔርንም ፡ ፈተኑት ፥
የእስራኤልንም ፡ ቅዱስ ፡ አሳዘኑት ።
፵፪ እነርሱም ፡ እጁን ፡ አላሰቡም ፥
ከጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡ ያዳነበትን ፡ ቀን ፥
፵፫ በግብጽ ፡ ያደረገውን ፡ ተአምራቱን ፥
በጣኔዎስም ፡ በረሃ ፡ ያደረገውን ፡ ድንቁን ።
፵፬ ወንዞቻቸውንም ፡ ወደ ፡ ደም ፡ ለወጠ ፥
ምንጮቻቸውን ፡ ደግሞ ፡ እንዳይጠጡ ።
፵፭ ዝንቦችንም ፡ በላያቸው ፡ሰደደባቸው ፥ በሉአ
ቸውም ፤
በጓጕንቸርም ፡ አጠፋቸው ።
፵፮ ፍሬያቸውን ፡ ለኵብኵብ ፥
ሥራቸውንም ፡ ለአንበጣ ፡ ሰጠ ።
፵፯ ወይናቸውን ፡ በበረዶ ፥
በለሳቸውንም ፡ በአመዳይ ፡ አጠፋ ።
፵፰ እንስሶቻቸውን ፡ ለበረዶ ፥
ሀብታቸውንም ፡ ለእሳት ፡ ሰጠ ።
፵፱ የመዓቱን ፡ መቅሠፍት ፡ በላያቸው ፡ ሰደደ ፤
መቅሠፍትን ፡ መዓትንም ፡ መከራንም ፡
በክፉዎች ፡ መላእክት ፡ ሰደደ ።
፶ ለቍጣው ፡ መንገድን ፡ ጠረገ ፤
ነፍሳቸውንም ፡ ከሞት ፡ አላዳናትም ፥
እንስሶቻቸውንም ፡ በሞት ፡ ውስጥ ፡ ዘጋ ፤
፶፩ በኵሮቻቸውን ፡ ሁሉ ፡ በግብጽ ፥
የድካማቸውንም ፡ መጀመሪያ ፡ በካም ፡ ድንኳ
ኖች ፡ ገደለ ።
፶፪ ሕዝቡን ፡ ግን ፡ እንደ ፡ በጎች ፡ አሰማራቸው ፥
እንደ ፡ መንጋም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ መራቸው ።
፶፫ በተስፋም ፡ መራቸው ፡ አልፈሩምም ፥
ጠላቶቻቸውንም ፡ በሕር ፡ ደፈናቸው ።
፶፬ ወደ ፡ መቅደሱም ፡ ተራራ ፡ አገባቸው ፥
ቀኙ ፡ ወደ ፡ ፈጠረችው ፡ ወደዚህች ፡ ተራራ ፤
፶፭ ከፊታቸውም ፡ አሕዛብን ፡ አባረረ ፥
ርስቱንም ፡ በገመድ ፡ አካፈላቸው ፥
የእስራኤልንም ፡ ወገኖች ፡ በቤታቸው ፡ አኖረ ።
፶፮ ነገር ፡ ግን ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈተኑት ፡
አስቈጡትም ፥ ምስክሩንም ፡ አልጠበቁም ፤
፶፯ ተመለሱም ፡ እንደ ፡ አባቶቻቸውም ፡ ከዱ ፤
እንደ ፡ ጠማማ ፡ ቀስትም ፡ ተገለበጡ ፤
፶፰ በኰረብታ ፡ መስገጃዎቻቸውም ፡ አስቈጡት ፥
በተቀረጹ ፡ ምስሎቻቸውም ፡ አስቀኑት ።
፶፱ እግዚአብሔርም ፡ ይህን ፡ ሰምቶ ፡ ተቈጣ ፥
እስራኤልንም ፡ እጅግ ፡ናቀ ፤
፷ የሴሎምን ፡ ማደሪያ ፡ ተዋት ፡
በሰዎች ፡ መካከል ፡ ያደረገባትን ፡ ድንኳኑን ፤
፷፩ ኃይላቸውን ፡ ለምርኮ ፥
ክልማቱንም ፡ በጠላት ፡ እጅ ፡ ሰጠ ።
፷፪ ሕዝቡንም ፡ በጦር ፡ ውስጥ ፡ ዘጋቸው ፥
ርስቱንም ፡ ቸል ፡ አላቸው ።
፷፫ ጕልማሶቻቸውን ፡ እሳት ፡ በላቸው ፥
ቈነጃጅቶቻቸውም ፡ አላዘኑም ፤
፷፬ ካህናቶቻቸውም ፡ በሰይፍ ፡ ወደቁ ፥
ባልቴቶቻቸውም ፡ አላለቀሱላቸውም ።
፷፭ እግዚአብሔርም ፡ ከእንቅልፍ ፡ እንደሚነቃ ፡
ተነሣ ፥
የወይን ፡ ስካር ፡ እንደ ፡ ተወው ፡ እንደ ፡ ኃያልም ፡
ሰው ፤
፷፮ ጠላቶቹንም ፡ በኋላቸው ፡ መታ ፤
የዘላለምን ፡ ኀሣር ፡ ሰጣቸው ።
፷፯ የዮሴፍንም ፡ ድንኳን ፡ ተዋት ፥
የኤፍሬምንም ፡ ወገን ፡ አልመረጠውም ፤
፷፰ የይሁዳን ፡ ወገን ፡ ግን ፡ መረጠ ፥
የወደደውን ፡ የጽዮንን ፡ ተራራ ።
፷፱ መቅደሱን ፡ እንደ ፡ አርያም ፡ ሠራ ፥
ለዘላለምም ፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡ መሠረታት ።
፸ ዳዊትንም ፡ ባሪያውን ፡ መረጠው ፥
ከበጎቹም ፡ መንጋ ፡ ውስጥ ፡ ወሰደው ፤
፸፩ ከሚያጠቡ ፡ በጎችም ፡ በኋላ ፥
ባሪያውን ፡ ያዕቆብን ፡
ርስቱንም ፡ እስራኤልን ፡ ይጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ወሰ
ደው ።
፸፪ በልቡ ፡ ቅንነት ፡ ጠበቃቸው ፥
በእጁም ፡ ብልሃት ፡ መራቸው ።

## መዝሙር ፡ ፸፰ ። (፸፱)

የአሳፍ ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ፥ አሕዛብ ፡ ወደ ፡ ርስትህ ፡ ገቡ ፤
የቅድስናህንም ፡ መቅደስ ፡ አረከሱ ፥
ኢየሩሳሌምንም ፡ እንደ ፡ መደብ ፡ አደረጉአት ።
፪ የባሪያዎችህንም ፡ በድኖች ፡ ለሰማይ ፡ ወፎች ፡
መብል ፡ አደረጉ ፥
የጻድቃንህንም ፡ ሥጋ ፡ ለምድር ፡ አራዊት ፤
፫ ደማቸውንም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ዙሪያ ፡ እንደ ፡
ውኃ ፡ አፈሰሱ ፥
የሚቀብራቸውም ፡ አጡ ።

፬፤ ለጎረቤቶቻችንም ፡ ስድብ ፡ ሆንን ፥
በዙሪያችንም ፡ ላሉ ፡ ማቅና ፡ ዘበት ።
፭፤ አቤቱ ፥ እስከ ፡ መቼ ፡ ለዘላለም ፡ ትቈጣለህ?
ቅንዓትህም ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ይነድዳል ?
፮፤ ስምህን ፡ በማይጠሩ ፡ መንግሥታት ፡ ላይ ፥
በማያውቁህም ፡ አሕዛብ ፡ ላይ ፡ መዓትህን ፡ አፍስስ ፤
፯፤ ያዕቆብን ፡ በልተውታልና ፥
ስፍራውንም ፡ ባድማ ፡ አድርገዋልና ።
፰፤ የቀደመውን ፡ በደላችንን ፡ አታስብብን ፥
ምሕረትህ ፡ በቶሎ ፡ ታግኘን ፥
እጅግ ፡ ተቸግረናልና ።
፱፤ አምላካችንና ፡ መድኃኒታችን ፡ ሆይ ፥ እርዳን ፤
ስለ ፡ ስምህ ፡ ክብር ፥ አቤቱ ፥ ታደገን ፥
ስለ ፡ ስምህም ፡ ኃጢአታችንን ፡ አስተስርይልን ።
፲፤ አሕዛብ ፡— አምላካቸው ፡ ወዴት ፡ ነው ? እንዳ ይሉ ፥
የፈሰሰውን ፡ የባሪያዎችህን ፡ ደም ፡ በቀል ፡
በዓይኖቻችን ፡ ፊት ፡ አሕዛብ ፡ ይወቁ ።
፲፩፤ የእስረኞች ፡ ጩኸት ፡ ወደ ፡ ፊትህ ፡ ይግባ ፤
እንደ ፡ ክንድህም ፡ ታላቅነት ፡ ሊገደሉ ፡ የተፈ ረደባቸውን ፡ አድን ።
፲፪፤ አቤቱ ፥ የተዘባበቱብህን ፡ መዘባበታቸውን ፡
ለጎረቤቶቻችን ፡ ሰባት ፡ እጥፍ ፡ በብብታቸው ፡ ክፈላቸው ።
፲፫፤ እኛ ፡ ሕዝብህ ፡ ግን ፥ የማሰማርያህም ፡ በጎች ፥
ለዘላለም ፡ እናመሰግንሃለን ፤
ለልጅ ፡ ልጅም ፡ ምስጋናህን ፡ እንናገራለን ።

## መዝሙር ፡ ፸፱ ። (፹)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በመለከቶች ፤ ስለ ፡ አሦራውያን ፤ የአሳፍ ፡ የምስክር ፡ መዝሙር ።

፩፤ ዮሴፍን ፡ እንደ ፡ መንጋ ፡ የምትመራ ፥
የእስራኤል ፡ ጠባቂ ፡ ሆይ ፥ አድምጥ ፤
በኪሩቤል ፡ ላይ ፡ የምትቀመጥ ፥ ተገለጥ ።
፪፤ በኤፍሬምና ፡ በብንያም ፡ በምናሴም ፡
ኃይልህን ፡ አንሣ ፡ እኛንም ፡ ለማዳን ፡ ና ።
፫፤ አቤቱ ፥ መልሰን ፥
ፊትህንም ፡ አብራ ፥ እኛም ፡ እንድናለን ።
፬፤ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ፥
በባሪያህ ፡ ጸሎት ፡ ላይ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ትቈጣለህ ?
፭፤ የእንባ ፡ እንጀራን ፡ ትመግበናለህ ፥
እንባም ፡ በስፍር ፡ ታጠጣናለህ ።
፮፤ ለጎረቤቶቻችን ፡ ክርክር ፡ አደረግኸን ፥
ጠላቶቻችንም ፡ በላያችን ፡ ተሣለቁብን ።
፯፤ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ፥ መልሰን ፥
ፊትህንም ፡ አብራ ፥ እኛም ፡ እንድናለን ።
፰፤ ከግብጽ ፡ የወይን ፡ ግንድ ፡ አመጣህ ፤
አሕዛብን ፡ አባረርህ ፡ እርስዋንም ፡ ተከልህ ።
፱፤ በፊትዋም ፡ ስፍራን ፡ አዘጋጀህ ፥
ሥሮችዋንም ፡ ተከልህ ፡ ምድርንም ፡ ሞላች ።
፲፤ ጥላዋ ፡ ተራሮችን ፡ ከደነ ፥
ጫፎችዋም ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዝግባ ፡ ሆኑ ።
፲፩፤ ቅርንጫፎችዋንም ፡ እስከ ፡ ባሕር ፥
ቡቃያዋንም ፡ እስከ ፡ ወንዝ ፡ ዘረጋች ።
፲፪፤ አጥርዋን ፡ ለምን ፡ አፈረስህ ?
መንገድ ፡ አላፊም ፡ ሁሉ ፡ ይቀጥፉታል ።
፲፫፤ የዱር ፡ እርያ ፡ አረከሳት ፥
የአገር ፡ አውሬም ፡ ተሰማራባት ።
፲፬፤ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ እንግዲህ ፡ ተመለስ ፤
ከሰማይ ፡ ተመልከት ፥ እይም ፥
ይህችንም ፡ የወይን ፡ ግንድ ፡ ጐብኝ ።
፲፭፤ በሰው ፡ ልጅ ፡ ለአንተ ፡ ያጸናኸውን ፡
ቀኝህ ፡ የተከላትን ፡ አንሣ ።
፲፮፤ በእሳት ፡ ተቃጥላለች ፡ ተነቅላማለች ፡
ከፊትህ ፡ ተግሣጽም ፡ የተነሣ ፡ ይጠፋሉ ።
፲፯፤ ለአንተ ፡ በጸናኸው ፡ በሰው ፡ ልጅ ፡ ላይ ፥
በቀኝህ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ እጅህ ፡ ትሁን ።
፲፰፤ ከአንተም ፡ አንራቅ ፤
አድነን ፡ ስምህንም ፡ እንጠራለን ።
፲፱፤ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ፥ መልሰን ፥
ፊትህንም ፡ አብራ ፥ እኛም ፡ እንድናለን ።

## መዝሙር ፡ ፹ ። (፹፩)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በዋሽንት ፤ የአሳፍ ፡ መዝሙር ።

፩፤ በረድኤታችን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፥
ለያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ እልል ፡ በሉ ።
፪፤ ዝማሬውን ፡ አንሡ ፡ ከበሮንም ፡ ስጡ ፥
ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡ በገና ፡ ከመሰንቆ ፡ ጋር ፤
፫፤ በመባቻ ፡ ቀን ፡ በከፍተኛው ፡ በዓላችን ፡ ቀን ፡
መለከትን ፡ ንፉ ፤
፬፤ ለእስራኤል ፡ ሥርዓቱ ፡ ነውና ፥
የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ ፍርድ ።
፭፤ ከግብጽ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ለዮሴፍ ፡ ምስክር ፡ አቆመው ።
ያላወቅሁትን ፡ ቋንቋ ፡ ሰማሁ ።
፮፤ ጫንቃውን ፡ ከሸክም ፥
እጆቹንም ፡ በቅርጫት ፡ ከመገዛት ፡ አራቅሁ ።
፯፤ በመከራህ ፡ ጊዜ ፡ ጠራኸኝ ፡ አዳንሁህም ፥
በተሰወረ ፡ ዐውሎም ፡ መለስሁልህ ፥
በክርክር ፡ ውኃ ፡ ዘንድም ፡ ፈተንሁህ ።
፰፤ ሕዝቤ ፡ ሆይ ፥ ስማኝ ፡ እነግርሃለሁም ፤
እስራኤል ፡ ሆይ ፥ እመሰክርልሃለሁ ።
፱፤ አንተስ ፡ ብትሰማኝ ፡ ሌላ ፡ አምላክ ፡ አይሆንልህም ፥
ለሌላ ፡ አምላክም ፡ አትሰግድም ።
፲፤ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ያወጣሁህ ፡
እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ ነኝና ፤
አፍህን ፡ አስፋ ፡ እሞላዋለሁም ።
፲፩፤ ሕዝቤ ፡ ግን ፡ ቃሌን ፡ አልሰሙኝም ፥
እስራኤልም ፡ አላዳመጠኝም ።
፲፪፤ እንደ ፡ ልባቸው ፡ ሥራ ፡ ተውኋቸው ፥
በልባቸውም ፡ አሳብ ፡ ሄዱ ።
፲፫፤ ሕዝቤስ ፡ ሰምቶኝ ፡ ቢሆን ፥
እስራኤልም ፡ በመንገዴ ፡ ሄደው ፡ ቢሆን ፤
፲፬፤ ጠላቶቻቸውን ፡ ፈጥኜ ፡ ባዋረድኋቸው ፡ ነበር ፥

በሚያስጨንቋቸውም ፡ ላይ ፡ እጄን ፡ በጣልሁ ፡ ነበር ፤

፲፭፤ የእግዚአብሔር ፡ ጠላቶችም ፡ በተገዙለት ፡ ነበር ፥
ዘመናቸውም ፡ ለዘላለም ፡ በሆነ ፡ ነበር ፤

፲፮፤ ከስንዴም ፡ ስብ ፡ ባበላቸው ፡ ነበር ፥
ከዓለቱም ፡ ማር ፡ ባጠገባቸው ፡ ነበር ።

## መዝሙር ፡ ፹፩ ። (፹፪)

የአሳፍ ፡ መዝሙር ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ በአማልክት ፡ ማኅበር ፡ ቆመ ፥
በአማልክትም ፡ መካከል ፡ ይፈርዳል ።

፪፤ እስከ ፡ መቼ ፡ ሐሰትን ፡ ትፈርዳላችሁ ?
እስከ ፡ መቼስ ፡ ለኃጢአተኞች ፡ ፊት ፡ ታደላላችሁ ?

፫፤ ለድሆችና ፡ ለድሀ ፡ አደጎች ፡ ፍረዱ ፤
ለችግረኛውና ፡ ለምስኪኑ ፡ ጽድቅ ፡ አድርጉ ፤

፬፤ ብቸኛውንና ፡ ችግረኛውን ፡ አድኑ ፤
ከኃጢአተኞችም ፡ እጅ ፡ አስጥሉአቸው ።

፭፤ አያውቁም ፥ አያስተውሉም ፤
በጨለማ ፡ ውስጥ ፡ ይመላለሳሉ ፤
የምድር ፡ መሠረቶች ፡ ሁሉ ፡ ተናወጡ ።

፮፤ እኔ ፡ ግን ፡— አማልክት ፡ ናችሁ ፥
ሁላችሁም ፡ የልዑል ፡ ልጆች ፡ ናችሁ ፤

፯፤ ነገር ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ትሞታላችሁ ፥
ከአለቆችም ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ትወድቃላችሁ ፡ አልሁ ።

፰፤ አቤቱ ፥ ተነሥ ፥ በምድር ፡ ላይ ፡ ፍረድ ፥
አንተ ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ ትወርሳለህና ።

## መዝሙር ፡ ፹፪ ። (፹፫)

የአሳፍ ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ፥ እንደ ፡ አንተ ፡ ማን ፡ ነው ?
አቤቱ ፥ ዝም ፡ አትበል ፥ ቸልም ፡ አትበል ።

፪፤ እነሆ ፥ ጠላቶችህ ፡ ጮኸዋልና ፥
የሚጠሉህም ፡ ራሳቸውን ፡ አንሥተዋልና ።

፫፤ ሕዝብህን ፡ በምክር ፡ ሸነገሉአቸው ፥
በቅዱሳንህም ፡ ላይ ፡ ተማከሩ ።

፬፤ ኑ ፡ ከሕዝብ ፡ እናጥፉቸው ፥
ደግሞም ፡ የእስራኤል ፡ ስም ፡ አይታሰብ ፡ አሉ ።

፭፤ አንድ ፡ ሆነው ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ተማከሩ ፤
በአንተ ፡ ላይ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረጉ ፤

፮፤ የኤዶማውያን ፡ ድንኳኖች ፡ እስማኤላውያንም ፥
ሞዓብም ፡ አጋራውያንም ፥

፯፤ ጌባል ፡ አሞንም ፡ አማሌቅም ፥
ፍልስጥኤማውያንም ፡ ከጢሮስ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፤

፰፤ አሦርም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ተባበረ ፥
ለሎጥ ፡ ልጆችም ፡ ረዳት ፡ ሆኑአቸው ።

፱፤ እንደ ፡ ምድያምና ፡ እንደ ፡ ሲሣራ ፥
በቂሶንም ፡ ወንዝ ፡ እንደ ፡ ኢያቢስ ፡ አድርግባቸው ።

፲፤ በዓይንዶር ፡ ጠፉ ፥
እንደ ፡ ምድርም ፡ ጕድፍ ፡ ሆኑ ።

፲፩፤ አለቆቻቸውን ፡ እንደ ፡ ሔሬብና ፡ እንደ ፡ ዜብ ፥
ታላላቆቻቸውንም ፡ እንደ ፡ ዛብሄልና ፡ እንደ ፡ ስልማና ፡ አድርጋቸው ፡—

፲፪፤ የእግዚአብሔርን ፡ መሠዊያ ፡ እንወርሳለን ፡ የሚሉትን ።

፲፫፤ አምላኬ ፡ ሆይ ፥ እንደ ፡ ትቢያ ፡
በነፋስ ፡ ፊትም ፡ እንደ ፡ ገለባ ፡ አድርጋቸው ።

፲፬፤ እሳት ፡ ዱርን ፡ እንደሚያቃጥል ፥
ነበልባልም ፡ ተራሮችን ፡ እንደሚያነድድ ፥

፲፭፤ እንዲሁ ፡ በቍጣህ ፡ አሳድዳቸው ፥
በመቅሠፍትህም ፡ አስደንግጣቸው ።

፲፮፤ ፊታቸውን ፡ እፍረት ፡ሙላው ፥
አቤቱ ፥ ስምህንም ፡ ይፈልጋሉ ።

፲፯፤ ይፈሩ ፡ ለዘላለሙም ፡ ይታወኩ ፤
ይጐስቍሉ ፡ ይጥፉም ።

፲፰፤ ስምህም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥
በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይም ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ ልዑል ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ ይወቁ ።

## መዝሙር ፡ ፹፫ ። (፹፬)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ በዋሽንት ፤ የቆሬ ፡ ልጆች ፡ መዝሙር ።

፩፤ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ ማደሪያዎችህ ፡ እንደምን ፡ የተወደዱ ፡ ናቸው !

፪፤ ነፍሴ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ አደባባዮች ፡ ትወድዳለች ፡ ትናፍቅማለች ፤
ልቤም ፡ ሥጋዬም ፡ በሕያው ፡ አምላክ ፡ ደስ ፡ ተሰኘ ።

፫፤ ወፍ ፡ ለእርስዋ ፡ ቤትን ፡ አገኘች ፥
ዋኖስም ፡ ጫጩቶችዋን ፡ የምታኖርበት ፡ ቤት ፡ አገኘች ፤
የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ንጉሤም ፡ አምላኬም ፡ ሆይ ፥
እርሱ ፡ መሠዊያህ ፡ ነው ።

፬፤ በቤትህ ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ፤
ለዓለምና ፡ ለዘላለምም ፡ ያመሰግኑሃል ።

፭፤ አቤቱ ፥ እርዳታው ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ የሆነለት ፥
በልቡም ፡ የላይኛውን ፡ መንገድ ፡ የሚያስብ ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ።

፮፤ በልቅሶ ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ በወሰነው ፡ ስፍራ ፡
የሕግ ፡ መምህር ፡ በረከትን ፡ ይሰጣልና ።

፯፤ ከኃይል ፡ ወደ ፡ ኃይል ፡ ይሄዳሉ ፤
የአማልክት ፡ አምላክ ፡ በጽዮን ፡ ይታያል ።

፰፤ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ፥ ጸሎቴን ፡ ስማ ፤
የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ አድምጥ ።

፱፤ አቤቱ ፥ መታመናችንን ፡ እይልን ፥
ወደ ፡ ቀባኸውም ፡ ፊት ፡ ተመልከት ።

፲፤ ከአእላፍ ፡ ይልቅ ፡ በአደባባዮችህ ፡ አንዲት ፡ ቀን ፡ ትሻላለች ፤
በኀጥአን ፡ ድንኳኖች ፡ ከመቀመጥ ፡ ይልቅ ፥
በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እጣል ፡ ዘንድ ፡ መረጥሁ ።

፲፩፤ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ምሕረትንና ፡ እውነትን ፡ ስለ ፡ ወደደ ፥
ሞገስንና ፡ ክብርን ፡ ይሰጣል ፤

እግዚአብሔር ፡ በቅንነት ፡ የሚሄዱትን ፡
ከመልካም ፡ ነገር ፡ አያሳጣቸውም ።
፲፪ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷
በአንተ ፡ የታመነ ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ።

## መዝሙር ፡ ፹፬ ። (፹፭)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የቆሬ ፡ ልጆች ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ÷ ለምድርህ ፡ ሞገስን ፡ አደረግህ ÷
የያዕቆብንም ፡ ምርኮ ፡ መለስህ ።
፪ የሕዝብህን ፡ ኃጢአት ፡ አስቀረህ ÷
አበሳቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ከደንህ ።
፫ መዓትህንም ፡ ሁሉ ፡ አስወገድህ ፤
ከቍጣህ ፡ መቅሠፍት ፡ ተመለስህ ።
፬ የመድኃኒታችን ፡ አምላክ ፡ ሆይ ÷ መልሰን ÷
ቍጣህንም ፡ ከእኛ ፡ መልስ ።
፭ በውኑ ፡ ለዘላለም ፡ ትቈጣናለህን ?
ቍጣህንስ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ታስረዝማለህን ?
፮ አቤቱ ÷ ትመለሳለህ ፡ ታድነንማለህ ፤
ሕዝብም ፡ በአንተ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፯ አቤቱ ÷ ምሕረትህን ፡ አሳየን ÷
አቤቱ ÷ መድኃኒትህንም ፡ ስጠን ።
፰ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ የሚናገረውን ፡ እሰማለሁ ፤
ሰላምን ፡ ለሕዝቡና ፡ ለቅዱሳኑ ፡
ልባቸውንም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ለሚመልሱ ፡ ይናገራልና ።
፱ ነገር ፡ ግን ፡ ክብር ፡ በምድራችን ፡ ያድር ፡ ዘንድ ፡
ማዳኑ ፡ ለሚፈሩት ፡ ቅርብ ፡ ነው ።
፲ ምሕረትና ፡ እውነት ፡ ተገናኙ ፤
ጽድቅና ፡ ሰላም ፡ ተስማሙ ።
፲፩ እውነት ፡ ከምድር ፡ በቀለች ÷
ጽድቅም ፡ ከሰማይ ፡ ተመለከተች ።
፲፪ እግዚአብሔርም ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ ይሰጣል ÷
ምድራችንም ፡ ፍሬዋን ፡ ትሰጣለች ።
፲፫ ጽድቅ ፡ በፊቱ ፡ ይሄዳል ÷
ፍለጋውንም ፡ በመንገድ ፡ ውስጥ ፡ ያኖራል ።

## መዝሙር ፡ ፹፭ ። (፹፮)

የዳዊት ፡ ጸሎት ።

፩ አቤቱ ÷ ጆሮህን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አዘንብል ፡ አድምጠኝም ÷
ችግረኛና ፡ ምስኪን ፡ ነኝና ።
፪ ቅዱስ ፡ ነኝና ፡ ነፍሴን ፡ ጠብቅ ፤
አምላኬ ፡ ሆይ ÷ አንተን ፡ የታመነውን ፡ ባሪያህን ፡ አድነው ።
፫ አቤቱ ÷ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እጮኻለሁና ፡ ማረኝ ።
፬ የባሪያህን ፡ ነፍስ ፡ ደስ ፡ አሰኛት ÷
አቤቱ ÷ ነፍሴን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ አነሣለሁና ።
፭ አቤቱ ÷ አንተ ፡ መሐሪና ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ ነህና ÷
ምሕረትህም ፡ ለሚጠሩህ ፡ ሁሉ ፡ ብዙ ፡ ነውና ።
፮ አቤቱ ÷ ጸሎቴን ፡ አድምጥ ÷
የልመናዬንም ፡ ድምፅ ፡ ስማ ።
፯ ትመልስልኛለህና ፡ በመከራዬ ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እጠራለሁ ።
፰ አቤቱ ÷ ከአማልክት ፡ የሚመስልህ ፡ የለም ÷
እንደ ፡ ሥራህም ፡ ያለ ፡ የለም ።
፱ ያደረግሃቸው ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ይመጣሉ ÷
አቤቱ ÷ በፊትህም ፡ ይሰግዳሉ ÷
ስምህንም ፡ ያከብራሉ ፤
፲ አቤቱ ÷ ድንቅ ፡ የምታደርግ ፡ አንተ ፡ ታላቅ ፡ ነህና ÷
አንተም ፡ ብቻህን ፡ ታላቅ ፡ አምላክ ፡ ነህና ።
፲፩ አቤቱ ÷ መንገድህን ፡ ምራኝ ÷
በእውነትህም ፡ እሄዳለሁ ፤
ስምህን ፡ ለመፍራት ፡ ልቤ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።
፲፪ አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ÷ በልቤ ፡ ሁሉ ፡ አመሰግንሃለሁ ÷
ለዘላለምም ፡ ስምህን ፡ አከብራለሁ ፤
፲፫ ምሕረትህ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ናትና ÷
ነፍሴንም ፡ ከታችኛይቱ ፡ ሲኦል ፡ አድነሃታልና ።
፲፬ አቤቱ ÷ ዓመፀኞች ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ተነሥተዋል ÷
የክፉዎችም ፡ ማኅበር ፡ ነፍሴን ፡ ፈለጉአት ፤
በፊታቸውም ፡ አላደረጉህም ።
፲፭ አቤቱ ÷ አንተ ፡ ግን ፡ መሐሪና ፡ ርኅሩኅ ፡ አምላክ ፡ ነህ ፤
መዓትህ ፡ የራቀ ፡ ምሕረትህም ፡ እውነትህም ፡ የበዛ ፤
፲፮ ወደ ፡ እኔ ፡ ተመልከት ፡ ማረኝም ፤
ለባሪያህ ፡ ኃይልህን ፡ ስጥ ÷ የሴት ፡ ባሪያህንም ፡ ልጅ ፡ አድን ።
፲፯ ምልክትንም ፡ ለመልካም ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ አድርግ ፤
የሚጠሉኝ ፡ ይዩ ፡ ይፈሩም ÷
አቤቱ ÷ አንተ ፡ ረድተኸኛልና ÷ አጽንተኸኛልምና ።

## መዝሙር ፡ ፹፮ ። (፹፯)

የቆሬ ፡ ልጆች ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩ መሠረቶቹ ፡ በተቀደሱ ፡ ተራሮች ፡ ናቸው ፤
፪ ከያዕቆብ ፡ ድንኳኖች ፡ ይልቅ ÷
እግዚአብሔር ፡ የጽዮንን ፡ ደጆች ፡ ይወድዳቸዋል ።
፫ የእግዚአብሔር ፡ ከተማ ፡ ሆይ ÷ በአንቺ ፡ የተከበረ ፡ ነገር ፡ ይባላል ።
፬ የሚያውቁኝን ፡ ረዓብንና ፡ ባቢሎንን ፡ አስባቸዋለሁ ፤
እነሆ ÷ ፍልስጥኤማውያን ፡ ጢሮስም ፡ የኢትዮጵያም ፡ ሕዝብ ÷
እነዚህ ፡ በዚያ ፡ ተወለዱ ።
፭ ሰው ፡ እናታችን ፡ ጽዮን ፡ ይላል ÷
በውስጥዋም ፡ ሰው ፡ ተወለደ ፤
እርሱ ፡ ራሱም ፡ ልዑል ፡ መሠረታት ።
፮ እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ÷
በውስጥዋም ፡ ለተወለዱት ፡ አለቆችዋ ፡ በመጽሐፍ ፡ ይነግራቸዋል ።
፯ በአንቺ ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ እንደሚላቸው ፡ ይነግራቸዋል ።

## መዝሙር ፡ ፹፯ ። (፹፰)

የቆሬ ፡ ልጆች ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።
ለመዘምራን ፡ አለቃ ፡ በማኅላት ፡ ለመዘመር ፤
የይዝራኤላዊው ፡ የኤማን ፡ ትምህርት ።

፩፤ አቤቱ ÷ የመድኃኒቴ ፡ አምላክ ÷
በቀንና ፡ በሌሊት ፡ በፊትህ ፡ ጮኽሁ ፤
፪፤ ጸሎቴ ፡ ወደ ፡ ፊትህ ፡ ትግባ ÷
ጆሮህንም ፡ ወደ ፡ ጩኸቴ ፡ አዘንብል ፤
፫፤ ነፍሴ ፡ መከራን ፡ ጠግባለችና ÷
ሕይወቴም ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ቀርባለችና ።
፬፤ ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ ከሚወርዱ ፡ ጋር ፡ ተቈጠርሁ ÷
ረዳትም ፡ እንደሌለው ፡ ሰው ፡ ሆንሁ ።
፭፤ ለዘላለም ፡ እንደማታስባቸው ÷
እንደ ፡ ተገደሉና ፡ በመቃብር ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ ተጣሉ ÷
በሙታን ፡ ውስጥ ፡ እንዳሉ ፡ የተጣልሁ ፡ ሆንሁ ፤
እነርሱም ፡ ከእጅህ ፡ ተለዩ ።
፮፤ በጨለማና ፡ በሞት ፡ ጥላ ፡ ውስጥ ÷
በታችኛው ፡ ጕድጓድ ፡ አስቀመጥኸኝ ።
፯፤ በእኔ ፡ ላይ ፡ ቍጣህ ፡ ጸና ÷
መቅሠፍትህን ፡ ሁሉ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ አመጣህ ።
፰፤ የሚያውቁኝን ፡ ከእኔ ፡ አራቅህ ፤
በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ርኩስ ፡ አደረግኸኝ ፤
ያዙኝ ÷ መውጫም ፡ የለኝም ።
፱፤ ዓይኖቼም ፡ በመከራ ፡ ፈዘዙ ፤
አቤቱ ÷ ሁልጊዜ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኽሁ ÷
እጆቼንም ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ዘረጋሁ ።
፲፤ በውኑ ፡ ለሙታን ፡ ተአምራት ፡ ታደርጋለህን ?
የሞቱትስ ፡ ተነሥተው ፡ ያመሰግኑሃልን ?
፲፩፤ በመቃብርስ ፡ ውስጥ ፡ ቸርነትህን ÷
እውነትህንስ ፡ በጥፋት ፡ ስፍራ ፡ ይናገራሉን ?
፲፪፤ ተአምራትህ ፡ በጨለማ ÷
ጽድቅህም ፡ በመርሳት ፡ ምድር ፡ ትታወቃለችን?
፲፫፤ አቤቱ ÷ እኔ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኽሁ ፤
በጥዋት ፡ ጸሎቴ ፡ ወደ ፡ ፊትህ ፡ ትደርሳለች ።
፲፬፤ አቤቱ ÷ ነፍሴን ፡ ለምን ፡ ትጥላለህ ?
ፊትህንስ ፡ ከእኔ ፡ ለምን ፡ ትሰውራለህ ?
፲፭፤ እኔ ፡ ከታናሽነቴ ፡ ችግረኛ ፡ ለሞትም ፡ የቀረብሁ ፡ ነኝ ፤
ከፍ ፡ ከፍ ፡ ካልሁ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ተዋረድሁ ፡ ተናቅሁም ።
፲፮፤ መቅሠፍትህ ፡ በላዬ ፡ አለፈ ÷
ግርማህም ፡ አስደነገጠኝ ።
፲፯፤ ሁልጊዜ ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ ከበቡኝ ÷
በአንድነትም ፡ ያዙኝ ።
፲፰፤ ወዳጆችንና ፡ ባልንጀራዬን ፡
ዘመዶቼንም ፡ ከመከራ ፡ የተነሣ ፡ ከእኔ ፡ አራቅህ ።

## መዝሙር ፡ ፹፰ ። (፹፱)

የይዝራኤላዊው ፡ የኤታን ፡ ትምህርት ።

፩፤ አቤቱ ÷ ምሕረትህን ፡ ለዘላለም ፡ እዘምራለሁ ÷
እውነትህንም ፡ በአፌ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ እናገራለሁ ።
፪፤ እንዲህ ፡ ብለሃልና ፡— ምሕረት ፡ ለዘላለም ፡ ይመሠረታል ÷
እውነትህም ፡ በሰማይ ፡ ይጸናል ።
፫፤ ከመረጥሁት ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ አደረግሁ ÷
ለባሪያዬም ፡ ለዳዊት ፡ ማልሁ ፡—
፬፤ ዘርህን ፡ ለዘላለም ፡ አዘጋጃለሁ ÷
ዙፋንህንም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ እመሠርታለሁ ።
፭፤ አቤቱ ÷ ሰማያት ፡ ተአምራትህን ፡
እውነትህንም ፡ ደግሞ ፡ በቅዱሳን ፡ ማኅበር ፡ ያመሰግናሉ ።
፮፤ እግዚአብሔርን ፡ በሰማይ ፡ የሚተካከለው ፡ ማን ፡ ነው ?
ከአማልክትስ ፡ ልጆች ፡ እግዚአብሔርን ፡ ማን ፡ ይመስለዋል ?
፯፤ በቅዱሳን ፡ ምክር ፡ እግዚአብሔር ፡ ክቡር ፡ ነው ፤
በዙሪያው ፡ ባሉት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ታላቅና ፡ ግሩም ፡ ነው ።
፰፤ አቤቱ ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ÷ እንደ ፡ አንተ ፡ ያለ ፡ ማን ፡ ነው ?
አቤቱ ÷ አንተ ፡ ብርቱ ፡ ነህ ÷ እውነትህም ፡ ይከብብሃል ።
፱፤ የባሕርን ፡ ኃይል ፡ አንተ ፡ ትገዛለህ ÷
የሞገዱንም ፡ መናወጥ ፡ አንተ ፡ ዝም ፡ ታሰኛለህ ።
፲፤ አንተ ፡ ረዓብን ፡ እንደ ፡ ተገደለ ፡ አዋረድኸው ÷
በኃይልህም ፡ ክንድ ፡ ጠላቶችህን ፡ በተንሃቸው ።
፲፩፤ ሰማያት ፡ የአንተ ፡ ናቸው ÷ ምድርም ፡ የአንተ ፡ ናት ፤
ዓለምንና ፡ ሞላውም ፡ አንተ ፡ መሠረትህ ።
፲፪፤ ሰሜንንና ፡ ደቡብን ፡ አንተ ፡ ፈጠርህ ፤
ታቦርና ፡ አርሞንዔም ፡ በስምህ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፲፫፤ ክንድህ ፡ ከኃይልህ ፡ ጋር ፡ ነው ፤
እጅህ ፡ በረታች ፡ ቀኝህም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለች ።
፲፬፤ የዙፋንህ ፡ መሠረት ፡ ጽድቅና ፡ ፍርድ ፡ ነው ፤
ምሕረትና ፡ እውነት ፡ በፊትህ ፡ ይሄዳሉ ።
፲፭፤ እልልታ ፡ የሚያውቅ ፡ ሕዝብ ፡ ምስጉን ፡ ነው ፤
አቤቱ ÷ በፊትህ ፡ ብርሃን ፡ ይሄዳሉ ።
፲፮፤ በስምህ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ÷
በጽድቅህም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላሉ ፤
፲፯፤ የኃይላቸው ፡ ትምክሕት ፡ አንተ ፡ ነህና ÷
በሞገስህም ፡ ቀንዳችን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላልና ።
፲፰፤ ረድኤታችን ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ከንጉሣችንም ፡ ከእስራኤል ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ።
፲፱፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ለልጆችህ ፡ በራእይ ፡ ተናገርህ ፡
እንዲህም ፡ አልህ ፡— ረድኤቴን ፡ በኃያል ፡ ላይ ፡ አኖርሁ ፤
ከሕዝቤ ፡ የተመረጠውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረግሁ ።
፳፤ ባሪያዬን ፡ ዳዊትን ፡ አገኘሁት ÷
ቅዱስ ፡ ዘይትም ፡ ቀባሁት ።
፳፩፤ እጄም ፡ ትረዳዋለች ÷
ክንዴም ፡ ታጸናዋለች ።
፳፪፤ ጠላት ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ አይጠቀምም ÷
የዓመፃ ፡ ልጅም ፡ መከራ ፡ አይጨምርበትም ።
፳፫፤ ጠላቶቹን ፡ ከፊቱ ፡ አጠፋለሁ ÷

የሚጠሉትንም ፡ አዋርዳቸዋለሁ ።
፳፬፡ እውነቴና ፡ ምሕረቴም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነው ÷
በስሜም ፡ ቀንዱ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
፳፭፡ እጁን ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡
ቀኙንም ፡ በወንዞች ፡ ላይ ፡ አኖራለሁ ።
፳፮፡ እርሱ ፡— አባቴ ፡ አንተ ፡ ነህ ÷
አምላኬ ፡ የመድኃኒቴም ፡ መጠጊያ ፡ ይላል ።
፳፯፡ እኔም ፡ ደግሞ ፡ በኵሬ ፡ አደርገዋለሁ ÷
ከምድር ፡ ነገሥታትም ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
፳፰፡ ለዘላለምም ፡ ምሕረቴን ፡ ለእርሱ ፡ እጠብቃለሁ ÷
ኪዳኔም ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ የታመነ ፡ ነው ።
፳፱፡ ዘሩንም ፡ ለዓለምና ፡ ለዘላለም ÷
ዙፋኑንም ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ዘመን ፡ አደርጋለሁ ።
፴፡ ልጆቹ ፡ ግን ፡ ሕጌን ፡ ቢተዉ ÷
በፍርዴም ፡ ባይሄዱ ፤
፴፩፡ ሥርዓቴንም ፡ ቢያረክሱ ÷
ትእዛዜንም ፡ ባይጠብቁ ፤
፴፪፡ ኃጢአታቸውን ፡ በበትር ÷
በደላቸውንም ፡ በመቅሠፍት ፡ እጐበኛታለሁ ።
፴፫፡ ምሕረቴን ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ አላርቅም ÷
በእውነቴም ፡ አልበድልም ፤
፴፬፡ ኪዳኔንም ፡ አላረክስም ÷
ከከንፈሬም ፡ የወጣውን ፡ አልለውጥም ።
፴፭፡ ዳዊትን ፡ እንዳልዋሸው ፡
አንድ ፡ ጊዜ ፡ በቅዱስነቴ ፡ ማልሁ ።
፴፮፡ ዘሩ ፡ ለዘላለም ÷
ዙፋኑም ፡ በፊቴ ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡ ይኖራል ።
፴፯፡ ለዘላለም ፡ እንደ ፡ ጨረቃ ፡ ይጸናል ፤
ምስክርነቱ ፡ በሰማይ ፡ የታመነ ፡ ነው ።
፴፰፡ አንተ ፡ ግን ፡ ናቅኸው ፡ ጣልኸውም ÷
የቀባኸውንም ፡ ጣልኸው ።
፴፱፡ የባሪያህንም ፡ ኪዳን ፡ አፈረስህ ÷
መቅደሱንም ፡ በምድር ፡ አረከስህ ።
፵፡ ቅጥሩን ፡ ሁሉ ፡ ጣልህ ÷
አምባዎቹንም ፡ አጠፋህ ።
፵፩፡ መንገድ ፡ አላፊም ፡ ሁሉ ፡ ተናጠቀው ÷
ለጎረቤቶቹም ፡ ስድብ ፡ ሆነ ።
፵፪፡ የጠላቶቹንም ፡ ቀኝ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረግህ ÷
ጠላቶቹንም ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ አሰኘህ ።
፵፫፡ የሰይፉንም ፡ ረድኤት ፡ መለስህ ÷
በሰልፍም ፡ ውስጥ ፡ አልደገፍኸውም ።
፵፬፡ ከንጽሕናውም ፡ ሻርኸው ÷
ዙፋኑንም ፡ በምድር ፡ ጣልህ ።
፵፭፡ የዙፋኑንም ፡ ዘመን ፡ አሳነስህ ÷
በእፍረትም ፡ ሸፈንኸው ።
፵፮፡ አቤቱ ÷ እስከ ፡ መቼ ፡ ለዘላለም ፡ ፊትህን ፡ ትመልሳለህ ?
እስከ ፡ መቼስ ፡ ቍጣህ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ይነድዳል ?
፵፯፡ ችሎታዬ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስብ ፤
በውኑ ፡ የሰውን ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡ ለከንቱ ፡ ፈጠርኸውን ?
፵፰፡ ሕያው ፡ ሆኖ ፡ የሚኖር ÷ ሞትንስ ፡ የማያይ ፡ ማን ፡ ነው ?
ነፍሱንስ ፡ ከሲኦል ፡ እጅ ፡ የሚያድን ፡ ማን ፡ ነው ?
፵፱፡ ለዳዊት ፡ በእውነት ፡ የማልህ ÷
አቤቱ ÷ የቀድሞ ፡ ምሕረትህ ፡ ወዴት ፡ ነው ?
፶፡ አቤቱ ÷ የባሪያዎችህን ፡ ስድብ ÷
በብብቴ ፡ ብዙ ፡ አሕዛብን ፡ የተቀበልሁትን ÷
፶፩፡ አቤቱ ÷ ጠላቶችህ ፡ የሰደቡትን ፡
የቀባኸውን ፡ ዘመን ፡ የሰደቡትን ፡ አስብ ።
፶፪፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ይባረክ ። ይሁን ፡ ይሁን ።

## መዝሙር ፡ ~~፹፱~~ ። (፺)

የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ የሙሴ ፡ ጸሎት ።

፩፡ አቤቱ ÷ አንተ ፡ ለትውልድ ፡ ሁሉ ፡ መጠጊያ ፡ ሆንህልን ።
፪፡ ተራሮች ፡ ሳይወለዱ ÷ ምድርም ፡ ዓለምም ፡ ሳይሠሩ ÷
ከዘላለም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ አንተ ፡ ነህ ።
፫፡ ሰውን ፡ ወደ ፡ ኅሳር ፡ አትመልስም ፤
የሰው ፡ ልጆች ፡ ሆይ ÷ ተመለሱ ፡ ትላለህ ፤
፬፡ ሺህ ፡ ዓመት ፡ በፊትህ ፡ እንዳለፈች ፡ እንደ ፡ ትናንት ፡ ቀን ÷
እንደ ፡ ሌሊትም ፡ ትጋት ፡ ነውና ።
፭፡ ዘመኖች ፡ የተናቁ ፡ ይሆናሉ ÷
በማለዳም ፡ እንደ ፡ ሣር ፡ ያልፋል ።
፮፡ ማልዶ ፡ ያብባል ፡ ያልፋልም ÷
በሠርክም ፡ ጠውልጎና ፡ ደርቆ ፡ ይወድቃል ።
፯፡ እኛ ፡ በቍጣህ ፡ አልቀናልና ÷
በመዓትህም ፡ ደንግጠናልና ።
፰፡ የተሰወረውን ፡ ኃጢአታችንን ፡ በፊትህ ፡ ብርሃን ÷
በደላችንንም ፡ በፊትህ ፡ አስቀመጥህ ።
፱፡ ዘመናችን ፡ ሁሉ ፡ አልፎአልና ÷
እኛም ፡ በመዓትህ ፡ አልቀናልና ፤
ዘመኖቻችንም ፡ እንደ ፡ ሸረሪት ፡ ድር ፡ ይሆናሉ ።
፲፡ የዘመኖቻችንም ፡ ዕድሜ ፡ ሰባ ፡ ዓመት ÷
ቢበረታም ፡ ሰማንያ ፡ ዓመት ፡ ነው ፤
ቢበዛ ፡ ግን ፡ ድካምና ፡ መከራ ፡ ነው ፤
ከእኛ ፡ ቶሎ ፡ ያልፋልና ÷ እኛም ፡ እንገሠጻለንና ።
፲፩፡ የቍጣህን ፡ ጽናት ፡ ማን ፡ ያውቃል ?
ከቍጣህ ፡ ግርማ ፡ የተነሣ ፡ አለቁ ።
፲፪፡ በልብ ፡ ጥበብን ፡ እንድንማር ÷
ቀኝህን ፡ እንዲህ ፡ አስታውቀን ።
፲፫፡ አቤቱ ÷ ተመለስ ÷ እስከ ፡ መቼስ ፡ ነው ?
ስለ ፡ ባሪያዎችህም ፡ ተምዋገት ።
፲፬፡ በማለዳ ፡ ምሕረትህን ፡ እንጠግባለን ፤
በዘመናችን ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ይለናል ፡ ሐሤትም ፡ እናደርጋለን ።
፲፭፡ መከራ ፡ ባሳየኸን ፡ ዘመን ፡ ፋንታ ÷
ክፉም ፡ በየንባቸው ፡ ዘመኖች ፡ ፋንታ ፡ ደስ ፡ ይለናል ።
፲፮፡ ባሪያዎችህንና ፡ ሥራህን ፡ እይ ÷
ልጆቻቸውንም ፡ ምራ ።
፲፯፡ የአምላካችን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ብርሃን ፡ በላያችን ፡ ይሁን ።
የእጆቻችንንም ፡ ሥራ ፡ በላያችን ፡ አቅና ።

## መዝሙር ፡ ፺ ። (፺፩)

የዳዊት ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩፤ በልዑል ፡ መጠጊያ ፡ የሚኖር ፡
ሁሉን ፡ በሚችል ፡ አምላክ ፡ ጥላ ፡ ውስጥ ፡ ያድራል ።
፪፤ እግዚአብሔርን ፡— አንተ ፡ መታመኛዬ ፡ ነህ ፡ እለዋለሁ ፤
አምላኬና ፡ መሸሸጊያዬ ፡ ነው ÷ በእርሱም ፡ እታመናለሁ ።
፫፤ እርሱ ፡ ከአዳኝ ፡ ወጥመድ ፡
ከሚያስደነግጥም ፡ ነገር ፡ ያድንሃልና ።
፬፤ በላባዎቹ ፡ ይጋርድሃል ÷
በክንፎቹም ፡ በታች ፡ ትተማመናለህ ፤
እውነት ፡ እንደ ፡ ጋሻ ፡ ይከብብሃል ።
፭፤ ከሌሊት ፡ ግርማ ÷
በቀን ፡ ከሚበርር ፡ ፍላጻ ÷
፮፤ በጨለማ ፡ ከሚሄድ ፡ ክፉ ፡ ነገር ÷
ከአደጋና ፡ ከቀትር ፡ ጋኔን ፡ አትፈራም ።
፯፤ በአጠገብህ ፡ ሺህ ፡ በቀኝህም ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ይወድቃሉ ፤
ወደ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ አይቀርብም ።
፰፤ በዓይኖችህ ፡ ብቻ ፡ ትመለከታለህ ÷
የኀጥአንንም ፡ ብድራት ፡ ታያለህ ።
፱፤ አቤቱ ÷ አንተ ፡ ተስፋዬ ፡ ነህና ፤
ልዑልን ፡ መጠጊያህ ፡ አደረግህ ።
፲፤ ክፉ ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ አይቀርብም ÷
መቅሠፍትም ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ አይገባም ።
፲፩፤ በመንገድህ ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቁህ ፡ ዘንድ ፡
መላእክቱን ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ ያዝዛቸዋልና ፤
፲፪፤ እግርህም ፡ በድንጋይ ፡ እንዳትሰናከል ፡
በእጆቻቸው ፡ ያነሡሃል ።
፲፫፤ በተኵላና ፡ በእባብ ፡ ላይ ፡ ትጫማለህ ፤
አንበሳውንና ፡ ዘንዶውን ፡ ትረግጣለህ ።
፲፬፤ በእኔ ፡ ተማምኖአልና ፡ አስጥለዋለሁ ፤
ስሜንም ፡ አውቆአልና ፡ እጋርደዋለሁ ።
፲፭፤ ይጠራኛል ፡ እመልስለትማለሁ ÷
በመከራውም ፡ ጊዜ ፡ ከእርሱ ፡ ጋራ ፡ እሆናለሁ ፤
አድነዋለሁ ፡ አከብረውማለሁ ።
፲፮፤ ረጅምን ፡ ዕድሜ ፡ አጠግበዋለሁ ÷
ማዳኔንም ፡ አሳየዋለሁ ።

## መዝሙር ፡ ፺፩ ። (፺፪)

በሰንበት ፡ ቀን ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩፤ እግዚአብሔርን ፡ ማመስገን ፡ መልካም ፡ ነው ÷
ልዑል ፡ ሆይ ÷ ለስምህም ፡ ዝማሬ ፡ ማቅረብ ፤
፪፤ በማለዳ ፡ ምሕረትን ÷
በሌሊትም ፡ እውነትህን ፡ ማውራት ፡
፫፤ አሥር ፡ አውታር ፡ ባለው ፡ በበገና ÷
ከምስጋና ፡ ጋርም ፡ በመሰንቆ ።
፬፤ አቤቱ ÷ በሥራህ ፡ ደስ ፡ አሰኝተኸኛልና ፤
በእጅህም ፡ ሥራ ፡ ደስ ፡ ይለኛልና ።
፭፤ አቤቱ ÷ ሥራህ ፡ እጅግ ፡ ትልቅ ፡ ነው ÷
አሳብህም ፡ እጅግ ፡ ጥልቅ ፡ ነው ።
፮፤ ሰነፍ ፡ ሰው ፡ አያውቅም ÷
ልብ ፡ የሌለውም ፡ ይህን ፡ አያስተውለውም ።
፯፤ ኃጢአተኞች ፡ እንደ ፡ ሣር ፡ ሲበቅሉ ÷
ዓመፃ ፡ የሚያደርጉ ፡ ሁሉ ፡ ሲለመልሙ ÷
ለዘላለም ፡ ዓለም ፡ እንደሚጠፉ ፡ ነው ።
፰፤ አቤቱ ÷ አንተ ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ልዑል ፡ ነህ ፤
፱፤ አቤቱ ÷ እነሆ ÷ ጠላቶችህ ፡ ይጠፋሉና ÷
ዓመፃንም ፡ የሚሠሩ ፡ ሁሉ ፡ ይበተናሉና ።
፲፤ ቀንዴ ፡ እንደ ፡ ቀንድ ፡ እንዳለው ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ፤
ሽምግልናዬም ፡ በዘይት ፡ ይለመልማል ።
፲፩፤ ዓይኔም ፡ በጠላቶቼ ፡ ላይ ፡ አየች ÷
ጆሮዬም ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ በቆሙ ፡ በክፉዎች ፡ ላይ ፡ ሰማች ።
፲፪፤ ጻድቅ ፡ እንደ ፡ ዘንባባ ፡ ያፈራል ÷
እንደ ፡ ሊባኖስ ፡ ዝግባም ፡ ያድጋል ።
፲፫፤ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ተተክለዋል ÷
በአምላካችንም ፡ አደባባይ ፡ ውስጥ ፡ ይበቅላሉ ።
፲፬፤ ያን ፡ ጊዜ ፡ በለመለመ ፡ ሽምግልና ፡ ያፈራሉ ፤
ደስተኞችም ፡ ሆነው ፡ ይኖራሉ ።
፲፭፤ አምላኬ ፡ እግዚአብሔር ፡ እውነተኛ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይነግራሉ ÷
በእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ዓመፃ ፡ የለም ።

## መዝሙር ፡ ፺፪ ። (፺፫)

በሰንበት ፡ ቀን ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ ነገሠ ÷ ክብርንም ፡ ለበሰ ፤
እግዚአብሔር ፡ ኃይልን ፡ ለበሰ ÷ ታጠቀም ፤
ዓለምን ፡ እንዳትናወጥ ፡ አጸናት ።
፪፤ ዙፋንህ ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ የተዘጋጀ ፡ ነው ÷
አንተም ፡ ከዘላለም ፡ ነህ ።
፫፤ አቤቱ ÷ ወንዞች ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጉ ÷
ወንዞች ፡ ቃሎቻቸውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጉ ።
፬፤ ከብዙ ፡ ውኆች ፡ ድምፅ ፡
ከባሕርም ፡ ታላቅ ፡ ሞገድ ፡ ይልቅ ፡
እግዚአብሔር ፡ በከፍታው ፡ ድንቅ ፡ ነው ።
፭፤ ምስክርህ ፡ እጅግ ፡ የታመነ ፡ ነው ፤
አቤቱ ÷ እስከ ፡ ረጅም ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ ለቤትህ ፡ ቅድስና ፡ ይገባል ።

## መዝሙር ፡ ፺፫ ። (፺፬)

በአራተኛ ፡ ሰንበት ፡ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ የበቀል ፡ አምላክ ፡ ነው ፤
የበቀል ፡ አምላክ ፡ ተገለጠ ።
፪፤ የምድር ፡ ፈራጅ ፡ ሆይ ÷ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በል ፤
ለትዕቢተኞች ፡ ፍዳቸውን ፡ ክፈላቸው ።
፫፤ አቤቱ ÷ ኃጢአተኞች ፡ እስከ ፡ መቼ ?
ኃጢአተኞች ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ይጓደዳሉ ?
፬፤ ይከራከራሉ ÷ ዓመፃንም ፡ ይናገራሉ ፤
ዓመፃንም ፡ የሚያደርጉ ፡ ሁሉ ፡ ይናገራሉ ።
፭፤ አቤቱ ÷ ሕዝብህን ፡ አዋረዱ ÷
ርስትህንም ፡ አስቸገሩ ።
፮፤ ባልቴቲቱንና ፡ ድሀ ፡ አደጉን ፡ ገደሉ ÷

ስደተኛውንም ፡ ገደሉ ።

፯፤ እግዚአብሔር ፡ አያይም ፥
የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ አያስተውልም ፡ አሉ ።

፰፤ የሕዝብ ፡ ደንቆሮች ፡ ሆይ ፥ አስተውሉ ፤
ሰነፎችማ ፡ መቼ ፡ ይጠበበሉ ?

፱፤ ጆሮን ፡ የተከለው ፡ አይሰማምን ?
ዓይንን ፡ የሠራው ፡ አያይምን ?

፲፤ አሕዛብንስ ፡ የሚገሥጸው ፥
ለሰውም ፡ እውቀትን ፡ የሚያስተምረው ፡ እርሱ ፡
አይዘልፍምን ?

፲፩፤ የሰዎች ፡ አሳብ ፡ ከንቱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ያውቃል ።

፲፪፡፲፫፤ ለኃጢአተኛ ፡ ጕድጓድ ፡ እስኪቈፈር ፡ ድረስ ፡
ከክፉዎች ፡ ዘመናት ፡ ይወገድ ፡ ዘንድ ፥
አቤቱ ፥ አንተ ፡ የገሠጽኸው ፡
ሕግህንም ፡ ያስተማርኸው ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡
ነው ።

፲፬፤ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ አይጥልምና ፥
ርስቱንም ፡ አይተውምና ፡

፲፭፤ ፍርድ ፡ ወደ ፡ ጽድቅ ፡ እስኪመለስ ፡ ድረስ ፥
ልበ ፡ ቅኖችም ፡ ሁሉ ፡ ይከተሉአታል ።

፲፮፤ በክፉዎች ፡ ላይ ፡ ለእኔ ፡ የሚቆም ፡ ማን ፡ ነው ?
ዓመፅንስ ፡ በሚያደርጉ ፡ ላይ ፡ ለእኔ ፡ የሚከራ
ከር ፡ ማን ፡ ነው ?

፲፯፤ እግዚአብሔር ፡ የረዳኝ ፡ ባይሆን ፡
ነፍሴ ፡ ለጥቂት ፡ ጊዜ ፡ በሲኦል ፡ ባደረች ፡ ነበር ።

፲፰፤ እግሮቼ ፡ ተሰናከሉ ፡ ባልሁ ፡ ጊዜ ፥
አቤቱ ፥ ምሕረትህ ፡ ረዳኝ ።

፲፱፤ አቤቱ ፥ ለልቤ ፡ እንደ ፡ መከራዋ ፡ ብዛት ፡
ማጽናናትህ ፡ ነፍሴን ፡ ደስ ፡ አሰኛት ።

፳፤ በሕግ ፡ ላይ ፡ ዓመፅን ፡ የሚሠራ ፡
የዓመፅ ፡ ዙፋን ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ይሆና
ልን ?

፳፩፤ የጻድቅን ፡ ነፍስ ፡ ያደቡባታል ፥
በንጹሕ ፡ ደምም ፡ ይፈርዳሉ ።

፳፪፤ እግዚአብሔር ፡ መጠጊያ ፡ ሆነኝ ፥
አምላኬ ፡ የተስፋዬም ፡ ረዳት ፡ ነው ።

፳፫፤ እንደ ፡ በደላቸውም ፡ እንደ ፡ ክፋታቸውም ፡
ፍዳቸውን ፡ ይከፍላቸዋል ፥
አምላካችን ፡ እግዚአብሔርም ፡ ያጠፋቸዋል ።

## መዝሙር ፡ ፺፬ ። (፺፭)

የዳዊት ፡ ምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩፤ ኑ ፥ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይበለን ፤
ለአምላክ ፡ ለመድኃኒታችን ፡ እልል ፡ እንበል ።

፪፤ በምስጋና ፡ ወደ ፡ ፊቱ ፡ እንድረስ ፥
በዝማሬም ፡ ለእርሱ ፡ እልል ፡ እንበል ፤

፫፤ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ አምላክ ፡ ነውና ፥
በአማልክትም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ንጉሥ ፡
ነውና ።

፬፤ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ አይጥላቸውም ፤
የምድር ፡ ዳርቻዎችም ፡ በእጁ ፡ ውስጥ ፡ ናቸው ፥
የተራሮች ፡ ከፍታዎች ፡ የእርሱ ፡ ናቸው ።

፭፤ ባሕር ፡ የእርሱ ፡ ናት ፡ እርሱም ፡ አደረጋት ፥
የብስንም ፡ እጆቹ ፡ ሠሩአት ።

፮፤ ኑ ፥ እንስገድ ፡ ለእርሱም ፡ እንገዛ ፤
በእርሱ ፡ ባደረገን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እን
በርከክ ፤

፯፤ እርሱ ፡ አምላካችን ፡ ነውና ፥
እኛ ፡ የማሰማርያው ፡ ሕዝብ ፡ የእጁም ፡ በጎች ፡
ነንና ።

፰፤ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንደ ፡ ተፈታተኑት ፡ እንዳስቈ
ጡት ፡ ጊዜ ፥
ዛሬ ፡ ድምፁን ፡ ብትሰሙ ፡ ልባችሁን ፡ አታጽኑ ።

፱፤ የተፈታተኑኝ ፡ አባቶቻችሁ ፡
ፈተኑኝ ፡ ሥራዬንም ፡ አዩ ።

፲፤ ያችን ፡ ትውልድ ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ተቈጥቻት ፡
ነበር ፡—
ሁልጊዜ ፡ ልባቸው ፡ ይስታል ፥
እነርሱም ፡ መንገዴን ፡ አላወቁም ፡ አልሁ ።

፲፩፤ ወደ ፡ ዕረፍቴም ፡ እንዳይገቡ ፡ በቍጣዬ ፡ ማልሁ ።

## መዝሙር ፡ ፺፭ ። (፺፮)

ከምርኮ ፡ በኋላ ፡ ቤት ፡ በተሠራ ፡ ጊዜ ።

፩፤ ለእግዚአብሔር ፡ አዲስ ፡ ምስጋናን ፡ አመስግኑ ፤
ምድር ፡ ሁሉ ፥ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ።

፪፤ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ ስሙንም ፡ ባርኩ ፥
ዕለት ፡ ዕለትም ፡ ማዳኑን ፡ አውሩ ።

፫፤ ክብሩን ፡ ለአሕዛብ ፡
ተአምራቱንም ፡ ለወገኖች ፡ ሁሉ ፡ ንገሩ ፤

፬፤ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ምስጋናውም ፡ ብዙ ፡
ነውና ፥
በአማልክትም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የተፈራ ፡ ነውና ።

፭፤ የአሕዛብ ፡ አማልክት ፡ ሁሉ ፡ አጋንንት ፡ ናቸውና ፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ሰማያትን ፡ ሠራ ።

፮፤ ምስጋናና ፡ ውበት ፡ በፊቱ ፥
ቅዱስነትና ፡ ግርማ ፡ በመቅደሱ ፡ ውስጥ ፡
ናቸው ።

፯፤ የአሕዛብ ፡ ወገኖች ፥ ለእግዚአብሔር ፡ አምጡ ፥
ክብርንና ፡ ምስጋናን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አምጡ ፤

፰፤ ለስሙ ፡ የሚገባ ፡ ክብርን ፡ ለእግዚአብሔር ፡
አምጡ ፤
ቍርባን ፡ ያዙ ፡ ወደ ፡ አደባባዮችም ፡ ግቡ ።

፱፤ በቅድስናው ፡ ስፍራ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስገዱ ፤
ምድር ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ትነዋወጥ ።

፲፤ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡— እግዚአብሔር ፡ ነገሠ ፡
በሉ ።
እንዳይናወጥም ፡ ዓለሙን ፡ እርሱ ፡ አጸናው ፥
አሕዛብንም ፡ በቅንነት ፡ ይፈርዳል ።

፲፩፤ ሰማያት ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፥ ምድርም ፡ ሐሤ
ትን ፡ ታድርግ ፤
ባሕርና ፡ ሞላዋ ፡ ይናወጡ ፤

፲፪፤ በረሃ ፡ በእርስዋም ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ ሐሤትን ፡
ያድርጉ ፤
የዱር ፡ ዛፎች ፡ ሁሉ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ ፊት ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፤

፲፫፤ ይመጣልና ፤ በምድር ፡ ላይ ፡ ሊፈርድ ፡ ይመ
ጣልና ፤

እርሱም ፡ ዓለምን ፡ በጽድቅ ፡
አሕዛብንም ፡ በቅንነት ፡ ይፈርዳል ።

## መዝሙር ፡ ፺፮ ። (፺፯)

፩፤ እግዚአብሔር ፡ ነገሠ ፤ ምድር ፡ ሐሤትን ፡ ታድ
ርግ ÷
ብዙ ፡ ደሴቶችም ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ።
፪፤ ደመና ፡ ጭጋግም ፡ በዙሪያው ፡ ናቸው ፤
ጽድቅና ፡ ፍርድ ፡ የዙፋኑ ፡ መሠረት ፡ ናቸው ።
፫፤ እሳት ፡ በፊቱ ፡ ይሄዳል ÷
ጠላቶቹንም ፡ በዙሪያው ፡ ያቃጥላል ።
፬፤ መብረቆቹ ፡ ለዓለም ፡ አበሩ ፤
ምድር ፡ አየችና ፡ ተናወጠች ።
፭፤ ተራሮችም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ÷
ከምድር ፡ ሁሉ ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ሰም ፡
ቀለጡ ።
፮፤ ሰማያት ፡ የእርሱን ፡ ጽድቅ ፡ አወሩ ÷
አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ ክብሩን ፡ አዩ ።
፯፤ ለተቀረጸ ፡ ምስል ፡ የሚሰግዱ ፡ ሁሉ ÷
በጣዖቶቻቸውም ፡ የሚመኩ ፡ ይፈሩ ፤
መላእክቱ ፡ ሁሉ ÷ ስገዱለት ።
፰፤ አቤቱ ÷ ስለ ፡ ፍርድህ ፡
ጽዮን ፡ ሰምታ ፡ ደስ ፡ አላት ÷
የይሁዳም ፡ ሴት ፡ ልጆች ፡ ደስ ፡ አላቸው ፤
፱፤ አንተ ÷ እግዚአብሔር ÷ በምድር ፡ ላይ ፡ ሁሉ ፡
ልዑል ፡ ነህና ÷
በአማልክትም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡ ከፍ ፡
ከፍ ፡ ብለሃልና ።
፲፤ እግዚአብሔርን ፡ የምትወድዱ ÷ ክፋትን ፡ ጥሉ ፤
እግዚአብሔር ፡ የቅዱሳኑን ፡ ነፍሶች ፡ ይጠብ
ቃል ÷
ከኀጥኣንም ፡ እጅ ፡ ያድናቸዋል ።
፲፩፤ ብርሃን ፡ ለጻድቃን ÷
ደስታም ፡ ለልበ ፡ ቅኖች ፡ ወጣ ።
፲፪፤ ጻድቃን ÷ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ÷
ለቅድስናውም ፡ መታሰቢያ ፡ አመስግኑ ።

## መዝሙር ፡ ፺፯ ። (፺፰)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ ለእግዚአብሔር ፡ አዲስ ፡ ምስጋናን ፡ አመስግኑ ÷
እግዚአብሔር ፡ ተአምራትን ፡ አድርጓልና ፤
ቀኙ ፡ የተቀደሰም ፡ ክንዱ ፡ ለእርሱ ፡ ማዳን ፡
አደረገ ።
፪፤ እግዚአብሔር ፡ ማዳኑን ፡ አስታወቀ ÷
በአሕዛብም ፡ ፊት ፡ ጽድቁን ፡ ገለጠ ።
፫፤ ለያዕቆብ ፡ ምሕረቱን ፡
ለእስራኤልም ፡ ቤት ፡ እውነቱን ፡ አሰበ ፤
የምድር ፡ ዳርቻዎች ፡ ሁሉ ፡ የአምላካችንን ፡
ማዳን ፡ አዩ ።
፬፤ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ሆይ ÷ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡
በሉ ፤
አመስግኑ ÷ ደስ ፡ ይበላችሁ ÷ ዘምሩም ።
፭፤ ለእግዚአብሔር ፡ በመሰንቆ ÷
በመሰንቆና ፡ በዝማሬ ፡ ድምፅ ፡ ዘምሩ ።
፮፤ በዋሽንትና ፡ በመለከት ፡ ድምፅ ፡
በንጉሥ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እልል ፡ በሉ ።
፯፤ ባሕርና ፡ ሞላዋ ÷
ዓለምም ፡ በእርስዋም ፡ የሚኖሩ ፡ ይናወጡ ።
፰፤ ወንዞችም ፡ በአንድነት ፡ በእጅ ፡ ያጨብጭቡ ፤
ተራሮች ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ÷
፱፤ በምድር ፡ ሊፈርድ ፡ ይመጣልና ።
ለዓለምም ፡ በጽድቅ ፡
ለአሕዛብም ፡ በቅንነት ፡ ይፈርዳል ።

## መዝሙር ፡ ፺፰ ። (፺፱)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ ነገሠ ÷ አሕዛብ ፡ ይደንግጡ ፤
በኪሩቤል ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ÷ ምድር ፡ ትናወጥ ።
፪፤ እግዚአብሔር ፡ በጽዮን ፡ ታላቅ ፡ ነው ፤
እርሱም ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ።
፫፤ ግሩምና ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ፡
ሁሉ ፡ ታላቅ ፡ ስምህን ፡ ያመስግኑ ።
፬፤ የንጉሥ ፡ ክብር ፡ ፍርድን ፡ ይወድዳል ፤
አንተ ፡ ቅንነትን ፡ አጸናህ ÷
ለያዕቆብ ፡ ፍርድንና ፡ ጽድቅን ፡ አንተ ፡ አደ
ረግህ ።
፭፤ አምላካችንን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድ
ርጉት ÷
ቅዱስ ፡ ነውና ፡ ወደ ፡ እግሩ ፡ መረገጫ ፡ ስገዱ ።
፮፤ ሙሴና ፡ አሮን ፡ በካህናቱ ፡ ዘንድ ÷
ሳሙኤልም ፡ ስሙን ፡ በሚጠሩት ፡ ዘንድ ፡
ናቸው ፤
እግዚአብሔርን ፡ ጠሩት ÷ እርሱም ፡ መለሰ
ላቸው ።
፯፤ በደመና ፡ ዓምድም ፡ ተናገራቸው ፤
ምስክሩንና ፡ የሰጣቸውን ፡ ትእዛዝ ፡ ጠበቁ ።
፰፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ሆይ ÷ አንተ ፡ ሰማሃቸው ፤
አቤቱ ÷ አንተ ፡ ማርሃቸው ÷
ሥራቸውን ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ተበቀልሃቸው ።
፱፤ አምላካችንን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድ
ርጉት ÷
በቅዱስ ፡ ተራራውም ፡ ስገዱ ፤
አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ።

## መዝሙር ፡ ፺፱ ። (፻)

የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩፤ ምድር ፡ ሁሉ ÷ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ በሉ ÷
፪፤ በደስታም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተገዙ ÷
በሐሤትም ፡ ወደ ፡ ፊቱ ፡ ግቡ ።
፫፤ እግዚአብሔር ፡ እርሱ ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
እወቁ ፤
እርሱ ፡ ሠራን ፡ እኛም ፡ አይደለንም ፤
እኛስ ፡ ሕዝቡ ፡ የማሰማርያውም ፡ በጎች ፡ ነን ።
፬፤ ወደ ፡ ደጆቹ ፡ በመገዛት ÷
ወደ ፡ አደባባዮቹም ፡ በምስጋና ፡ ግቡ ፤
አመስግኑት ÷ ስሙንም ፡ ባርኩ ፤
፭፤ እግዚአብሔር ፡ ቸር ÷ ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ÷
እውነቱም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነውና ።

## መዝሙር ፡ ፻ ፡፡ (፻፩)

የዳዊት ፡ መዝሙር ፡፡

፩፤ አቤቱ ፥ ምሕረትንና ፡ ፍርድን ፡ እቀኝልሃለሁ ፡፡
፪፤ እዘምራለሁ ፥ ንጹሕ ፡ መንገድንም ፡ አስተውላለሁ ፤
ወደ ፡ እኔ ፡ መቼ ፡ ትመጣለህ ?
በቤቴ ፡ መካከል ፡ በልቤ ፡ ቅንነት ፡ እሄዳለሁ ፡፡
፫፤ በዓይኔ ፡ ፊት ፡ ክፉን ፡ ነገር ፡ አላኖርሁም ፤
ሕግ ፡ ተላላፊዎችን ፡ ጠላሁ ፡፡
፬፤ ጠማማ ፡ ልብም ፡ አልተጠጋኝም ፤
ክፉ ፡ ከእኔ ፡ በራቀ ፡ ጊዜ ፡ አላወቅሁም ፡፡
፭፤ ባልንጀራውን ፡ በቀስታ ፡ የሚያማን ፡ እርሱን ፡ አሳደድሁ ፤
በዓይኑ ፡ ትዕቢተኛ ፡ የሆነውና ፡ ልቡ ፡ የሚሳሳው ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ አይተባበርም ፡፡
፮፤ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡
ዓይኖቼ ፡ በምድር ፡ ምእመናን ፡ ላይ ፡ ናቸው ፤
በቀና ፡ መንገድ ፡ የሚሄድ ፡ እርሱ ፡ ያገለግለኛል ፡፡
፯፤ ትዕቢትን ፡ የሚያደርግ ፡ በቤቴ ፡ መካከል ፡ አይኖርም ፤
ዓመፅን ፡ የሚናገር ፡ በዓይኔ ፡ ፊት ፡ አይቀናም ፡፡
፰፤ ዓመፃ ፡ የሚያደርጉትን ፡ ሁሉ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ከተማ ፡ አጠፋቸው ፡ ዘንድ ፥
የምድርን ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሁሉ ፡ በማለዳ ፡ አገድላቸዋለሁ ፡፡

## መዝሙር ፡ ፻፩ ፡፡ (፻፪)

ባዘነና ፡ ልመናውን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ባፈሰሰ ፡ ጊዜ ፡ የችግረኛ ፡ ጸሎት ፡፡

፩፤ አቤቱ ፥ ጸሎቴን ፡ ስማኝ ፥
ጩኸቴም ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ይድረስ ፡፡
፪፤ በመከራዬ ፡ ቀን ፡ ፊትህን ፡ ከኔ ፡ አትመልስ ፤
ጆሮህን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አዘንብል ፤
በጠራሁህ ፡ ቀን ፡ ፈጥነህ ፡ ስማኝ ፡፡
፫፤ ዘመኔ ፡ እንደ ፡ ጢስ ፡ አልቃለችና ፥
አጥንቶቼም ፡ እንደ ፡ መቃጠያ ፡ ተቃጥለዋልና ፡፡
፬፤ እህል ፡ መብላት ፡ ተረስቶኛልና ፡
ተቀሠፍሁ ፡ ልቤም ፡ እንደ ፡ ሣር ፡ ደረቀ ፡፡
፭፤ ከጩኸቴ ፡ ድምፅ ፡ የተነሣ ፡ አጥንቶቼ ፡ ከሥጋዬ ፡ ጋር ፡ ተጣበቁ ፡፡
፮፤ እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ እርኩም ፡ መሰልሁ ፤
በፈረሰ ፡ ቤት ፡ እንዳለ ፡ እንደ ፡ ጕጕት ፡ ሆንሁ ፡፡
፯፤ ተጋሁ ፥ በሰገነትም ፡ እንደሚኖር ፡ ብቸኛ ፡ ድንቢጥ ፡ ሆንሁ ፡፡
፰፤ ጠላቶቼ ፡ ሁልጊዜ ፡ ይሰድቡኛል ፥
የሚያሳድዱኝም ፡ ተማማሉብኝ ፡፡
፱፤ አመድን ፡ እንደ ፡ እህል ፡ ቅሜአለሁና ፥
መጠጤንም ፡ ከእንባዬ ፡ ጋር ፡ ቀላቅያለሁና ፥
፲፤ ከቍጣህና ፡ ከመዓትህ ፡ የተነሣ ፤
አንሥተኸኛልና ፥ ጥለኸኛማልና ፡፡
፲፩፤ ዘመኖቼ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ አዘንብለዋል ፤
እኔም ፡ እንደ ፡ ሣር ፡ ደርቄአለሁ ፡፡
፲፪፤ አንተ ፡ ግን ፥ አቤቱ ፥ ለዘላለም ፡ ትኖራለህ ፥
መታሰቢያህም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡፡
፲፫፤ አንተ ፡ ተነሥ ፡ ጽዮንንም ፡ ይቅር ፡ በላት ፥
የምሕረትዋ ፡ ጊዜ ፡ ነውና ፥ ዘመንዋም ፡ ደርሶአልና !
፲፬፤ ባሪያዎችህም ፡ ድንጋዮችዋን ፡ ወድደዋልና ፥
ለመሬትዋም ፡ አዝነዋልና ፡፡
፲፭፤ አቤቱ ፥ አሕዛብ ፡ ስምህን ፥
ነገሥታትም ፡ ሁሉ ፡ ክብርህን ፡ ይፈራሉ ፤
፲፮፤ እግዚአብሔር ፡ ጽዮንን ፡ ይሠራታልና ፥
በክብሩም ፡ ይገለጣልና ፡፡
፲፯፤ ወደ ፡ ችግረኞች ፡ ጸሎት ፡ ተመለከተ ፥
ልመናቸውንም ፡ አልናቀም ፡፡
፲፰፤ ይህ ፡ ለሚመጣ ፡ ትውልድ ፡ ይጻፍ ፥
የሚፈጠርም ፡ ሕዝብ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ ይላል ፤
፲፱፤ እግዚአብሔር ፡ ከመቅደሱ ፡ ከፍታ ፡ ሆኖ ፡ ተመልክቶአልና ፥
ከሰማይ ፡ ሆኖ ፡ ምድርን ፡ አይቶአልና ፤
፳፤ የእስረኞችን ፡ ጩኸት ፡ ይሰማ ፡ ዘንድ ፥
ሊገደሉ ፡ የተፈረደባቸውን ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፤
፳፩፤ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ በጽዮን ፡
ምስጋናውንም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ይናገሩ ፡ ዘንድ ፤
፳፪፤ አሕዛብ ፡ በአንድነት ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡
መንግሥታትም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይገዙ ፡ ዘንድ ፡፡
፳፫፤ በኃይሉ ፡ ጎዳና ፡ መለሰለት ፡—
የዘመኔን ፡ አነስተኛነት ፡ ንገረኝ ፡፡
፳፬፤ በዘመኔ ፡ እኩሌታ ፡ አትውሰደኝ ፤
ዓመቶችህ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ናቸው ፡፡
፳፭፤ አቤቱ ፥ አንተ ፡ ከጥንት ፡ ምድርን ፡ መሠረትህ ፥
ሰማያትም ፡ የእጅህ ፡ ሥራ ፡ ናቸው ፡፡
፳፮፤ እነርሱ ፡ ይጠፋሉ ፥ አንተ ፡ ግን ፡ ትኖራለህ ፤
ሁላቸው ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ያረጃሉ ፥
እንደ ፡ መጐናጸፊያም ፡ ትለውጣቸዋለህ ፥ ይለወጡማል ፤
፳፯፤ አንተ ፡ ግን ፡ ያው ፡ አንተ ፡ ነህ ፥
ዓመቶችህም ፡ ከቶ ፡ አያልቁም ፡፡
፳፰፤ የባሪያዎችህም ፡ ልጆች ፡ ይኖራሉ ፥
ዘራቸውም ፡ ለዘላለም ፡ ትጸናለች ፡፡

## መዝሙር ፡ ፻፪ ፡፡ (፻፫)

የዳዊት ፡ መዝሙር ፡፡

፩፤ ነፍሴ ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ፥
አጥንቶቼም ፡ ሁሉ ፥ የተቀደሰ ፡ ስሙን ፡፡
፪፤ ነፍሴ ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ፥
ምስጋናውንም ፡ ሁሉ ፡ አትርሺ ፤
፫፤ ኃጢአትሽን ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡ የሚል ፥
ደዌሽንም ፡ ሁሉ ፡ የሚፈውስ ፥
፬፤ ሕይወትሽን ፡ ከጥፋት ፡ የሚያድናት ፥
በምሕረቱና ፡ በቸርነቱ ፡ የሚከልልሽ ፥
፭፤ ምኞትሽን ፡ ከበረከቱ ፡ የሚያጠግባት ፥
ጕልማስነትሽን ፡ እንደ ፡ ንስር ፡ ያድሳል ፡፡
፮፤ እግዚአብሔር ፡ ይቅርታ ፡ አድራጊ ፡ ነው ፤
ለተበደሉ ፡ ሁሉ ፡ ይፈርዳል ፡፡

፯፡ ለሙሴ ፡ መንገዱን ፡ አስታወቀ ፥
ለእስራኤል ፡ ልጆችም ፡ አደራረጉን ።
፰፡ እግዚአብሔር ፡ መሐሪና ፡ ይቅር ፡ በይ ፡ ነው ፥
ከቍጣ ፡ የራቀ ፡ ምሕረቱም ፡ የበዛ ።
፱፡ ሁልጊዜም ፡ አይቀሥፍም ፥ ለዘላለምም ፡ አይቈጣም ።
፲፡ እንደ ፡ ኃጢአታችን ፡ አላደረገብንም ፥
እንደ ፡ በደላችንም ፡ አልከፈለንም ።
፲፩፡ ሰማይ ፡ ከምድር ፡ ከፍ ፡ እንደሚል ፥
እንዲሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምሕረቱን ፡ በሚፈሩት ፡ ላይ ፡ አጠነከረ ።
፲፪፡ ምሥራቅ ፡ ከምዕራብ ፡ እንደሚርቅ ፥
እንዲሁ ፡ ኃጢአታችንን ፡ ከእኛ ፡ አራቀ ።
፲፫፡ አባት ፡ ለልጆቹ ፡ እንደሚራራ ፡
እንዲሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሚፈሩት ፡ ይራራል ፤
፲፬፡ ፍጥረታችንን ፡ እርሱ ፡ ያውቃልና ፤
አቤቱ ፥ እኛ ፡ አፈር ፡ እንደ ፡ ሆንን ፡ አስብ ።
፲፭፡ ሰውስ ፡ ዘመኑ ፡ እንደ ፡ ሣር ፡ ነው ፤
እንደ ፡ ዱር ፡ አበባ ፡ እንዲሁ ፡ ያብባል ፤
፲፮፡ ነፋስ ፡ በነፈሰበት ፡ ጊዜ ፡ ያልፋልና ፥
ስፍራውንም ፡ ደግሞ ፡ አያውቀውምና ።
፲፯፡ የእግዚአብሔር ፡ ምሕረት ፡ ግን ፡ ከዘላለም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ በሚፈሩት ፡ ላይ ፥
ጽድቁም ፡ በልጅ ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ነው ፤
፲፰፡ ቃል ፡ ኪዳኑን ፡ በሚጠብቁ ፥
ትእዛዙንም ፡ ያደርጉአት ፡ ዘንድ ፡ በሚያስቡ ፡ ላይ ፡ ነው ።
፲፱፡ እግዚአብሔር ፡ ዙፋኑን ፡ በሰማይ ፡ አዘጋጀ ፥
መንግሥቱም ፡ ሁሉን ፡ ትገዛለች ።
፳፡ ቃሉን ፡ የምትፈጽሙ ፥ ብርቱዎችና ፡ ኃያላን ፥
የቃሉንም ፡ ድምፅ ፡ የምትሰሙ ፡ መላእክቱ ፡ ሁሉ ፥
እግዚአብሔርን ፡ ባርኩ ።
፳፩፡ ሠራዊቱ ፡ ሁሉ ፥
ፈቃዱን ፡ የምታደርጉ ፡ አገልጋዮቹ ፥
እግዚአብሔርን ፡ ባርኩ ።
፳፪፡ ፍጥረቶቹ ፡ ሁሉ ፡ በግዛቱ ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፥
እግዚአብሔርን ፡ ባርኩ ።
ነፍሴ ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ።

## መዝሙር ፡ ፻፫ ። (፻፬)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፡ ነፍሴ ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ፤
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ነህ ፤
ክብርንና ፡ ግርማን ፡ ለበስህ ።
፪፡ ብርሃንን ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ለበስህ ፤
ሰማይንም ፡ እንደ ፡ መጋረጃ ፡ ዘረጋህ ፤
፫፡ እልፍኙን ፡ በውኃ ፡ የሚሠራ ፥
ሰረገላውን ፡ ደመና ፡ የሚያደርግ ፥
በነፋስ ፡ ክንፍም ፡ የሚሄድ ፥
፬፡ መላእክቱን ፡ መንፈስ ፡ የሚያደርግ ፥
አገልጋዮቹንም ፡ የእሳት ፡ ነበልባል ።
፭፡ ለዘላለም ፡ እንዳትናወጥ ፡
ምድርን ፡ በመሠረትዋ ፡ ላይ ፡ መሠረታት ።
፮፡ በጥልቅ ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ከደንሃት ፥
በተራሮችም ፡ ላይ ፡ ውኆች ፡ ይቆማሉ ።
፯፡ ከዘለፋህም ፡ ይሸሻሉ ፥
ከነጐድጓድህም ፡ ድምፅ ፡ ይደነግጣሉ ፤
፰፡ ወደ ፡ ተራሮች ፡ ይወጣሉ ፥
ወደ ፡ ቈላዎች ፡ ወዳዘጋጀህላቸው ፡ ስፍራ ፡ ይወርዳሉ ፤
፱፡ እንዳያልፉትም ፡ ድንበር ፡ አደረግህላቸው ፡
ምድርን ፡ ይከድኑ ፡ ዘንድ ፡ እንዳይመለሱ ።
፲፡ ምንጮችን ፡ ወደ ፡ ቈላዎች ፡ ይልካል ፤
በተራሮች ፡ መካከል ፡ ውኆች ፡ ያልፋሉ ፤
፲፩፡ የዱር ፡ አራዊትን ፡ ሁሉ ፡ ያጠጣሉ ፥
የበረሃ ፡ አህያዎችም ፡ ጥማታቸውን ፡ ይረካሉ ።
፲፪፡ የሰማይም ፡ ወፎች ፡ በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ያድራሉ ፥
በድንጋዩ ፡ ስንጥቅ ፡ መካከልም ፡ ይጮኻሉ ።
፲፫፡ ተራሮችን ፡ ከላይ ፡ የሚያጠጣቸው ፤
ከሥራህ ፡ ፍሬ ፡ ምድር ፡ ትጠግባለች ።
፲፬፡ እንጀራን ፡ ከምድር ፡ ያወጣ ፡ ዘንድ ፡
ለምለሙን ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ጥቅም ፥
ሣርንም ፡ ለእንስሳ ፡ ያበቅላል ።
፲፭፡ ወይን ፡ የሰውን ፡ ልብ ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፥
ዘይትም ፡ ፊትን ፡ ያበራል ፥
እህልም ፡ የሰውን ፡ ጕልበት ፡ ያጠነክራል ።
፲፮፡ የእግዚአብሔር ፡ ዛፎች ፡
እርሱም ፡ የተከላቸው ፡ የሊባኖስ ፡ ዝግባዎች ፡ ይጠግባሉ ።
፲፯፡ በዚያም ፡ ወፎች ፡ ይዋለዳሉ ፥
የሽመላ ፡ ቤትም ፡ የእነርሱ ፡ ጎረቤት ፡ ነው ።
፲፰፡ ረጃጅም ፡ ተራራዎች ፡ ለዋላዎች ፥
ድንጋዮችም ፡ ለእሽኮኮች ፡ መሸሸ ፡ ናቸው ።
፲፱፡ ጨረቃን ፡ ለጊዜዎች ፡ አደረገ ፤
ፀሐይም ፡ መግቢያውን ፡ ያውቃል ።
፳፡ ጨለማ ፡ ታደርጋለህ ፡ ሌሊትም ፡ ይሆናል ፤
በእርሱም ፡ የዱር ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ፡ ይወጡበታል ።
፳፩፡ የአንበሳ ፡ ግልገሎች ፡ ለመንጠቅ ፡ ይጮኻሉ ፥
ከእግዚአብሔርም ፡ ምግባቸውን ፡ ይሻሉ ።
፳፪፡ ፀሐይ ፡ ስትወጣ ፡ ይሰበሰባሉ ፥
በየዋሻቸውም ፡ ይተኛሉ ።
፳፫፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ተግባሩ ፥
እስኪመሽም ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ሥራው ፡ ይወጣል ።
፳፬፡ አቤቱ ፥ ሥራህ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነው ፤
ሁሉን ፡ በጥበብ ፡ አደረግህ ፥
ምድርም ፡ ከፍጥረትህ ፡ ተሞላች ።
፳፭፡ ይህች ፡ ባሕር ፡ ታላቅና ፡ ሰፊ ፡ ናት ፤
በዚያ ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌለው ፡ ተንቀሳቃሽ ፥
ታላላቆችና ፡ ታናናሾች ፡ እንስሶች ፡ አሉ ።
፳፮፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ መርከቦች ፡ ይሄዳሉ ፥
በዚያም ፡ ላይ ፡ የፈጠርኸው ፡ ዘንዶ ፡ ይጫወትበታል ።
፳፯፡ ምግባቸውን ፡ በየጊዜው ፡ ትሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡
እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ አንተን ፡ ተስፋ ፡ ያደርጋሉ ።
፳፰፡ በሰጠሃቸውም ፡ ጊዜ ፡ ይሰበስባሉ ፤

እጅህን ፡ ትከፍታለህ ፥ ከመልካም ፡ ነገርም ፡ ይጠግባሉ ።

፳፱ ፊትህን ፡ ስትሰውር ፡ ይደነግጣሉ ፤
ነፍሳቸውን ፡ ታወጣለህ ፡ ይሞታሉም ፥
ወደ ፡ አፈራቸውም ፡ ይመለሳሉ ።

፴ መንፈስህን ፡ ትልካለህ ፡ ይፈጠራሉም ፥
የምድርንም ፡ ፊት ፡ ታድሳለህ ።

፴፩ የእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ ለዘላለም ፡ ይሁን ፤
እግዚአብሔር ፡ በሥራው ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።

፴፪ ምድርን ፡ ያያል ፡ እንድትንቀጠቀጥም ፡ ያደርጋል ፤
ተራሮችን ፡ ይዳስሳል ፡ ይጤሳሉም ።

፴፫ በሕይወቴ ፡ ሳለሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እቀኛለሁ ፥
ለአምላኬም ፡ በምኖርበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ እዘምራለሁ ።

፴፬ ቃሌ ፡ ለእርሱ ፡ ይጣፍጠው ፥
እኔም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።

፴፭ ኀጥአን ፡ ከምድር ፡ ይጥፉ ፤
ዓመፀኞች ፡ እንግዲህ ፡ አይገኙ ።
ነፍሴ ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ። ሃሌ ፡ ሉያ ።

## መዝሙር ፡ ፻፬ ። (፻፭)

ሃሌ ፡ ሉያ ።

፩ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ ስሙንም ፡ ጥሩ ፥
ለአሕዛብም ፡ ሥራውን ፡ አውሩ ።

፪ ተቀኙለት ፥ ዘምሩለት ፥
ተአምራቱንም ፡ ሁሉ ፡ ተናገሩ ።

፫ በቅዱስ ፡ ስሙ ፡ ተጓደዱ ፤
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈልግ ፡ ልብ ፡ ደስ ፡ ይበለው ።

፬ እግዚአብሔርን ፡ ፈልጉት ፡ ትጸናላችሁም ፤
ሁልጊዜ ፡ ፊቱን ፡ ፈልጉ ።

፭ ፡ ፮ በረያዎቹ ፡ የአብርሃም ፡ ዘር ፥
ለእርሱም ፡ የተመረጣችሁ ፡ የያዕቆብ ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥
የሠራትን ፡ ድንቅ ፡ አስቡ ፥
ተአምራቱን ፡ የአፉንም ፡ ፍርድ ።

፯ እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችን ፡ ነው ፤
ፍርዱ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ነው ።

፰ ቃል ፡ ኪዳኑን ፡ ለዘላለም ፥
እስከ ፡ ሺህ ፡ ትውልድ ፡ ያዘዘውን ፡ ቃሉን ፡ አሰበ ፥

፱ ለአብርሃም ፡ ያደረገውን ፥
ለይስሐቅም ፡ የማለውን ፤

፲ ለያዕቆብ ፡ ሥርዓት ፡ እንዲሆን ፡
ለእስራኤልም ፡ የዘላለም ፡ ኪዳን ፡ እንዲሆን ፡ አጸና ፤

፲፩ እንዲህም ፡ አለ ፡— ለአንተ ፡ የከነዓንን ፡ ምድር ፡
የርስታችሁን ፡ ገመድ ፡ እሰጣለሁ ፤

፲፪ ይህም ፡ የሆነው ፡ እነርሱ ፡ በቍጥር ፡ ጥቂቶች ፡ ሰዎች ፥
እጅግ ፡ ጥቂቶችና ፡ ስደተኞች ፡ ሲሆኑ ፡ ነው ።

፲፫ ከሕዝብ ፡ ወደ ፡ ሕዝብ ፥
ከመንግሥትም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ሕዝብ ፡ አለፉ ።

፲፬ ፡ ፲፭ የቀባኋቸውን ፡ አትዳስሱ ፥
በነቢያቴም ፡ ክፉ ፡ አታድርጉ ፡ ብሎ ፥
ሰው ፡ ግፍ ፡ ያደርግባቸው ፡ ዘንድ ፡ አልፈቀደም ፥
ስለ ፡ እነርሱም ፡ ነገሥታትን ፡ ገሠጸ ።

፲፮ በምድር ፡ ላይ ፡ ራብን ፡ ጠራ ፥
የእህልን ፡ ኃይል ፡ ሁሉ ፡ ሰበረ ።

፲፯ በፊታቸው ፡ ሰውን ፡ ላከ ፤
ዮሴፍ ፡ ለባርነት ፡ ተሸጠ ።

፲፰ እግሮቹም ፡ በእግር ፡ ብረት ፡ ደከሙ ፥
እርሱም ፡ በብረት ፡ ውስጥ ፡ ገባ ።

፲፱ ቃሉ ፡ እስኪመጣለት ፡ ድረስ ፥
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ፈተነው ።

፳ ንጉሥ ፡ ላከ ፡ ፈታውም ፥
የአሕዛብም ፡ አለቃ ፡ አስፈታው ።

፳፩ የቤቱ ፡ ጌታ ፥
የጥሪቱ ፡ ሁሉ ፡ ገዢ ፡ አደረገው ፥

፳፪ አለቆቹን ፡ እንደ ፡ ፈቃዱ ፡ ይገሥጽ ፡ ዘንድ ፥
ሽማግሌዎቹንም ፡ ጥበበኞች ፡ ያደርጋቸው ፡ ዘንድ ።

፳፫ እስራኤልም ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ገባ ፥
ያዕቆብም ፡ በካም ፡ አገር ፡ ተቀመጠ ።

፳፬ ሕዝቡንም ፡ እጅግ ፡ አበዛ ፥
ከጠላቶቻቸውም ፡ ይልቅ ፡ አበረታቸው ።

፳፭ ሕዝቡን ፡ ይጠሉ ፡ ዘንድ ፡
በባሪያዎቹም ፡ ላይ ፡ ይተነኰሉ ፡ ዘንድ ፡ ልባቸውን ፡ ለወጠ ።

፳፮ ባሪያውን ፡ ሙሴን ፡
የመረጠውንም ፡ አሮንን ፡ ላከ ።

፳፯ የተአምራቱን ፡ ነገር ፡ በላያቸው ፡
ድንቁንም ፡ በካም ፡ አገር ፡ አደረገ ።

፳፰ ጨለማን ፡ ላከ ፡ ጨለመባቸውም ፤
በቃሉም ፡ ዐመፁ ።

፳፱ ውኃቸውን ፡ ወደ ፡ ደም ፡ ለወጠ ፥
ዓሦቻቸውንም ፡ ገደለ ።

፴ ምድራቸው ፡ የንጉሦቻቸውም ፡ ቤቶች ፡
በጓጕንቸር ፡ ሞሉ ።

፴፩ ተናገረ ፥ የውሻ ፡ ዝንብ ፡
ትንኝም ፡ በዳርቻቸው ፡ መጡ ።

፴፪ ዝናባቸውን ፡ በረዶ ፡ አደረገው ፥
እሳትም ፡ በምድራቸው ፡ ተቃጠለች ።

፴፫ ወይናቸውንና ፡ በለሳቸውን ፡ መታ ፥
የአገራቸውንም ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ሰበረ ።

፴፬ ተናገረ ፥ አንበጣም ፡
ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌለውም ፡ ኵብኵብ ፡ መጣ ፥

፴፭ የአገራቸውንም ፡ ለምለም ፡ ሁሉ ፡ በላ ፥
የምድራቸውንም ፡ ፍሬ ፡ በላ ።

፴፮ የአገራቸውንም ፡ በኵር ፡ ሁሉ ፥
የጕልበታቸውን ፡ መጀመሪያ ፡ ሁሉ ፡ መታ ።

፴፯ ከወርቅና ፡ ከብርም ፡ ጋር ፡ አወጣቸው ፥
በወገናቸውም ፡ ውስጥ ፡ ደዌ ፡ አልነበረም ።

፴፰ ፈርተዋቸው ፡ ነበርና ፡
ግብጽ ፡ በመውጣታቸው ፡ ደስ ፡ አላት ።

፴፱፤ ደመናን ፡ ለመሸፈኛ ፡ ዘረጋባቸው ፥
እሳትንም ፡ በሌሊት ፡ ያበራላቸው ፡ ዘንድ ፡ ዘረጋ ።
፵፤ ለመኑ ፥ ድርጭትንም ፡ አመጣላቸው ፥
የሰማይንም ፡ እንጀራ ፡ አጠጋባቸው ።
፵፩፤ ዓለቱን ፡ ሰነጠቀ ፥ ውኃውም ፡ ፈሰሰ ፤
ወንዞች ፡ በበረሃ ፡ ሄዱ ፤
፵፪፤ ለባሪያው ፡ ለአብርሃም ፡ የነገረውን ፡
ቅዱስ ፡ ቃሉን ፡ አስቦአልና ።
፵፫፤ ሕዝቡንም ፡ በደስታ ፡
የተመረጡትንም ፡ በእልልታ ፡ አወጣ ።
፵፬፤ የአሕዛብንም ፡ አገሮች ፡ ሰጣቸው ፥
የወገኖችንም ፡ ድካም ፡ ወረሱ ፥
፵፭፤ ሕጉን ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፥
ሥርዓቱንም ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ። ሃሌ ፡ ሉያ ።

## መዝሙር ፡ ፻፭ ። (፻፮)

፩፤ ሃሌ ፡ ሉያ ፤
ቸር ፡ ነውና ፥ ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፡
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ።
፪፤ የእግዚአብሔርን ፡ ኃይል ፡ ሥራ ፡ ማን ፡ ይናገ
ራል ?
ምስጋናውንስ ፡ ሁሉ ፡ ማን ፡ ያሰማል ?
፫፤ ፍርድን ፡ የሚጠብቁ ፥
ጽድቅንም ፡ ሁልጊዜ ፡ የሚያደርጉ ፡ ምስጉኖች ፡
ናቸው ።
፬፤ አቤቱ ፥ በሕዝብህ ፡ ሞገስ ፡ አስበን ፥
በመድኃኒትህም ፡ ጐብኘን ፤
፭፤ የመረጥሃቸውን ፡ በጎነት ፡ እናይ ፡ ዘንድ ፥
በሕዝብህም ፡ ደስታ ፡ ደስ ፡ ይለን ፡ ዘንድ ፥
ከርስትህም ፡ ጋር ፡ እንጓደድ ፡ ዘንድ ።
፮፤ ከአባቶቻችን ፡ ጋር ፡ ኃጢአት ፡ ሠራን ፥
ዐመፅንም ፥ በደልንም ።
፯፤ አባቶቻችን ፡ በግብጽ ፡ ሳሉ ፡ ተአምራትህን ፡
አላስተዋሉም ፥
የምሕረትህንም ፡ ብዛት ፡ አላሰቡም ፤
በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ ባለፉ ፡ ጊዜ ፡ ዐመፁብህ ።
፰፤ ኃይሉን ፡ ግን ፡ ለማስታወቅ ፡
ስለ ፡ ስሙ ፡ አዳናቸው ።
፱፤ የኤርትራንም ፡ ባሕር ፡ ገሠጸ ፡ እርሱም ፡ ደረቀ ፤
እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በጥልቅ ፡ መራቸው ።
፲፤ ከሚጠሉአቸውም ፡ እጅ ፡ አዳናቸው ፥
ከጠላትም ፡ እጅ ፡ ተቤዣቸው ።
፲፩፤ ያሳደዱአቸውንም ፡ ውኃ ፡ ደፈናቸው ፥
ከእነርሱም ፡ አንድ ፡ አልቀረም ።
፲፪፤ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በቃሉ ፡ አመኑ ፥
ምስጋናውንም ፡ ዘመሩ ።
፲፫፤ ፈጥነውም ፡ ሥራውን ፡ ረሱ ፥
በምክሩም ፡ አልታገሡም ።
፲፬፤ በምድረ ፡ በዳም ፡ ምኞትን ፡ ተመኙ ፥
በበረሃም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተፈታተኑት ።
፲፭፤ የለመኑትንም ፡ ሰጣቸው ፤
ለነፍሳቸው ፡ ግን ፡ ክሳትን ፡ ላከ ።
፲፮፤ ሙሴንም ፡ እግዚአብሔር ፡ የቀደሰውንም ፡ አሮ
ንን ፡
በሰፈር ፡ ተመቀኙአቸው ።
፲፯፤ ምድርም ፡ ተከፈተች ፡ ዳታንንም ፡ ዋጠችው ፥
የአቤሮንንም ፡ ወገን ፡ ደፈነች ፤
፲፰፤ በማኅበራቸውም ፡ እሳት ፡ ነደደች ፥
ነበልባልም ፡ ኃጥአንን ፡ አቃጠላቸው ።
፲፱፤ በኮሬብም ፡ ጥጃን ፡ ሠሩ ፥
ቀልጦ ፡ ለተሠራ ፡ ምስልም ፡ ሰገዱ ።
፳፤ ሣርም ፡ በሚበላ ፡ በበሬ ፡ ምሳሌ ፡
ክብራቸውን ፡ ለወጡ ።
፳፩፡፳፪፤ ታላቅ ፡ ነገርንም ፡ በግብጽ ፥
ድንቅንም ፡ በካም ፡ ምድር ፥
ግሩም ፡ ነገርንም ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ ያደረገ
ውን ፡
ያዳናቸውንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ረሱ ።
፳፫፤ እንዳያጠፋቸው ፡ ቍጣውን ፡ ይመልስ ፡ ዘንድ ፡
የተመረጠው ፡ ሙሴ ፡ በመቅሠፍት ፡ ጊዜ ፡
በፊቱ ፡ ባይቆም ፡ ኖሮ ፥
ያጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ ተናገረ ።
፳፬፤ የተወደደችውን ፡ ምድር ፡ ናቁ ፥
በቃሉም ፡ አልታመኑም ፥
፳፭፤ በድንኳኖቻቸውም ፡ ውስጥ ፡ አንጐራጐሩ ፤
የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አልሰሙም ።
፳፮፡፳፯፤ በምድረ ፡ በዳም ፡ ይጥላቸው ፡ ዘንድ ፥
ዘራቸውንም ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ይጥል ፡
ዘንድ ፥
በየአገሩም ፡ ይበትናቸው ፡ ዘንድ ፥
እጁን ፡ አነሣባቸው ።
፳፰፤ በብዔል ፡ ፌጎርም ፡ ተባበሩበት ፥
የሙታንንም ፡ መሥዋዕት ፡ በሉ ፤
፳፱፤ በሥራቸውም ፡ አስመረሩት ፥
ቸነፈርም ፡ በላያቸው ፡ በዛ ።
፴፤ ፊንሐስም ፡ ተነሥቶ ፡ ፈረደባቸው ፥
ቸነፈሩም ፡ ተወ ፤
፴፩፤ ያም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ጽድቅ ፡
ሆኖ ፡ ተቈጠረለት ።
፴፪፡፴፫፤ በክርክር ፡ ውኃ ፡ ዘንድም ፡ አስቈጡት ፥
መንፈሱን ፡ አስመርረዋታልና ፤
ስለ ፡ እነርሱም ፡ ሙሴ ፡ ተበሳጨ ፤
በከንፈሮቹም ፡ በስንፍና ፡ ተናገረ ።
፴፬፤ እግዚአብሔርም ፡ እንዳላቸው ፡ አሕዛብን ፡ አላ
ጠፉም ፤
፴፭፤ ከአሕዛብም ፡ ጋር ፡ ተደባለቁ ፥ ሥራቸውንም ፡
ተማሩ ።
፴፮፤ ለጣዖቶቻቸውም ፡ ተገዙ ፥ ወጥመድም ፡ ሆኑ
ባቸው ።
፴፯፤ ወንዶች ፡ ልጆቻቸውንና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸ
ውን ፡ ለአጋንንት ፡ ሠዉ ፤
፴፰፤ የወንዶች ፡ ልጆቻቸውንና ፡ የሴቶች ፡ ልጆቻ
ቸውን ፡ ደም ፥
ለከነዓን ፡ ጣዖቶች ፡ የሠዉአቸውን ፡ ንጹሕ ፡
ደም ፡ አፈሰሱ ፥
ምድርም ፡ በደም ፡ ረከሰች ።
፴፱፤ በሥራቸው ፡ ረከሱ ፥
በማድረጋቸውም ፡ አመነዘሩ ።

፵ ፡ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ነደደ ÷
ርስቱንም ፡ ተጸየፈ ።
፵፩ ፡ ወደ ፡ አሕዛብም ፡ እጅ ፡ አሳለፋቸው ÷
የሚጠሉአቸውም ፡ ገዙአቸው ።
፵፪ ፡ ጠላቶቻቸውም ፡ ግፍ ፡ አደረጉባቸው ÷
ከእጃቸውም ፡ በታች ፡ ተዋረዱ ።
፵፫ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ አዳናቸው ፤
ነገር ፡ ግን ፡ በምክራቸው ፡ አስመረሩት ÷
በኃጢአታቸውም ፡ ተዋረዱ ።
፵፬ ፡ እርሱ ፡ ግን ፡ ጩኸታቸውን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡
ጭንቀታቸውን ፡ ተመለከተ ፤
፵፭ ፡ ለእነርሱም ፡ ኪዳኑን ፡ አሰበ ÷
እንደ ፡ ምሕረቱም ፡ ብዛት ፡ ተጸጸተ ።
፵፮ ፡ በማረኩአቸውም ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ሞገስን ፡ ሰጣቸው ።
፵፯ ፡ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ÷ አድነን ፤
ቅዱስ ፡ ስምህን ፡ እናመሰግን ፡ ዘንድ ÷
በምስጋናህም ፡ እንመካ ፡ ዘንድ ÷
ከአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ሰብስበን ።
፵፰ ፡ ከዘላለም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ፤
ሕዝብም ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡ ይበል ። ሃሌ ፡ ሉያ ።

## መዝሙር ፡ ፻፯ ። (፻፮)

ሃሌ ፡ ሉያ ።

፩ ፡ ቸር ፡ ነውና ÷ ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፡
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፤
፪ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያዳናቸው ÷
ከጠላቶች ፡ እጅ ፡ ያዳናቸው ፡ ይናገሩ ።
፫ ፡ ከምሥራቅና ፡ ከምዕራብ ÷ ከሰሜንና ፡ ከባሕር ÷
ከየአገሩ ፡ ሰበሰባቸው ።
፬ ፡ ውኃ ፡ በሌለበት ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ተቅበዘበዙ ፤
የሚኖሩበትንም ፡ ከተማ ፡ መንገድ ፡ አላገኙም ።
፭ ፡ ተራቡ ፡ ተጠሙም ÷
ነፍሳቸውም ፡ በውስጣቸው ፡ አለቀች ።
፮ ፡ በተጨነቁ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ÷
ከመከራቸውም ፡ አዳናቸው ፤
፯ ፡ ወደሚኖሩበት ፡ ከተማ ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡
የቀና ፡ መንገድን ፡ መራቸው ።
፰ ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ስላደረገው ፡ ተአምራት ፡
ስለ ፡ ምሕረቱም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመስግኑ ፤
፱ ፡ የተራበችን ፡ ነፍስ ፡ አጥግቦአልና ÷
የተራቈተችንም ፡ ነፍስ ፡ በበረከት ፡ ሞልቶአልና ።
፲ ፡ በጨለማ ፡ በሞትም ፡ ጥላ ፡ የተቀመጡ ÷
በችግር ፡ በብረትም ፡ የታሰሩ ፤
፲፩ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስለ ፡ ዐመፁ ÷
የልዑልንም ፡ ምክር ፡ ስለ ፡ ናቁ ÷
፲፪ ፡ ልባቸው ፡ በድካም ፡ ተዋረደ ፤
ታመሙ ፡ የሚረዳቸውም ፡ አጡ ።
፲፫ ፡ በተጨነቁ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ÷
በመከራቸውም ፡ አዳናቸው ።
፲፬ ፡ ከጨለማና ፡ ከሞት ፡ ጥላ ፡ አወጣቸው ÷
እስራታቸውንም ፡ ሰበረ ።
፲፭ ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ስላደረገው ፡ ተአምራት ፡
ስለ ፡ ምሕረቱም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመስግኑ ፤
፲፮ ፡ የናሱን ፡ ደጆች ፡ ሰብሮአልና ÷
የብረቱንም ፡ መወርወሪያ ፡ ቈርጦአልና ።
፲፯ ፡ ስለ ፡ ዓመፃቸው ፡ ሰነፉ ÷
ስለ ፡ ኃጢአታቸውም ፡ ተቸገሩ ።
፲፰ ፡ ሰውነታቸው ፡ መብልን ፡ ሁሉ ፡ ተጸየፈች ÷
ወደ ፡ ሞትም ፡ ደጆች ፡ ቀረቡ ።
፲፱ ፡ በተጨነቁ ፡ ጊዜም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ÷
ከመከራቸውም ፡ አዳናቸው ።
፳ ፡ ቃሉን ፡ ላከ ፡ ፈወሳቸውም ÷
ከጥፋታቸውም ፡ አዳናቸው ።
፳፩ ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ስላደረገው ፡ ተአምራት ፡
ስለ ፡ ምሕረቱም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመስግኑ ፤
፳፪ ፡ የምስጋና ፡ መሥዋዕትንም ፡ ይሠውለት ÷
በእልልታም ፡ ሥራውን ፡ ይንገሩ ።
፳፫ ፡ በመርከቦች ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ የሚወርዱ ÷
በታላቅ ፡ ውኃ ፡ ሥራቸውን ፡ የሚሠሩ ÷
፳፬ ፡ እነርሱ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ÷
በጥልቅም ፡ ያለችውን ፡ ድንቁን ፡ አዩ ።
፳፭ ፡ ተናገረ ÷ ዐውሎ ፡ ነፋስም ፡ ተነሣ ÷
ሞገድም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ።
፳፮ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ይወጣሉ ፡ ወደ ፡ ጥልቅም ፡ ይወርዳሉ ፤
ነፍሳቸውም ፡ በመከራ ፡ ቀለጠች ።
፳፯ ፡ ደነገጡ ፡ እንደ ፡ ስካርም ፡ ተንገደገዱ ÷
ጥበባቸውም ፡ ሁሉ ፡ ተዋጠች ።
፳፰ ፡ በተጨነቁ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ÷
ከመከራቸውም ፡ አዳናቸው ።
፳፱ ፡ ዐውሎንም ፡ ጸጥ ፡ አደረገ ÷
ሞገዱም ፡ ዝም ፡ አለ ።
፴ ፡ ዝም ፡ ብሎአልና ፡ ደስ ፡ አላቸው ፤
ወደ ፡ ፈለጉትም ፡ ወደብ ፡ መራቸው ።
፴፩ ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ስላደረገው ፡ ተአምራት ፡
ስለ ፡ ምሕረቱም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመስግኑ ።
፴፪ ፡ በአሕዛብ ፡ ጉባኤ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያድርጉት ÷
በሽማግሌዎችም ፡ ሸንጎ ፡ ያመስግኑት ።
፴፫ ፡ ወንዞችን ፡ ምድረ ፡ በዳ ÷
የውኃውንም ፡ ምንጮች ፡ ደረቅ ፡ አደረጋቸው ፤
፴፬ ፡ ከተቀመጡባት ፡ ክፋት ፡ የተነሣ ፡
ፍሬያማዋን ፡ ምድር ፡ ጨው ፡ አደረጋት ።
፴፭ ፡ ምድረ ፡ በዳን ፡ ለውኃ ፡ መቆሚያ ÷
ደረቁንም ፡ ምድር ፡ የውኃ ፡ ምንጮች ፡ አደረገ ።
፴፮ ፡ በዚያም ፡ ራብተኞችን ፡ አስቀመጠ ÷
የሚኖሩበትንም ፡ ከተማ ፡ ሠሩ ።
፴፯ ፡ እርሻዎችንም ፡ ዘሩ ፡ ወይኖችንም ፡ ተከሉ ÷
የእህልንም ፡ ሰብል ፡ አደረጉ ።
፴፰ ፡ በረካቸውም ፡ እጅግም ፡ በዙ ፤
እንስሶቻቸውንም ፡ አላሳነሰባቸውም ።
፴፱ ፡ እነርሱ ፡ በችግር ፡ በክፋት ፡ በጭንቀት ፡ ተዋረዱ ፡ እያነሱም ፡ ሄዱ ፤
፵ ፡ በአለቆችም ፡ ላይ ፡ ኅሣርን ፡ አፈሰሰ ÷

መንገድም፡በሌለበት፡በምድረ፡በዳ፡አሳታቸው።
፵፩፤ ችግረኛንም ፡ ከችግሩ ፡ ረዳው ፤
እንደ ፡ በጎች ፡ መንጋ ፡ ወገን ፡ አደረገው ።
፵፪፤ ቅኖች ፡ ያያሉ ፥ ደስም ፡ ይላቸዋል ፤
ኃጢአትም ፡ ሁሉ ፡ አፍዋን ፡ ትዘጋለች ።
፵፫፤ ጥበበኛ ፡ የሆነና ፡ ይህን ፡ የሚጠብቅ ፡ ማን ፡ ነው ?
እርሱ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ምሕረት ፡ ያስተ
ውላል ።

## መዝሙር ፡ ፻፯ ። (፻፰)

የዳዊት ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩፤ ልቤ ፡ ጽኑ ፡ ነው ፥ አቤቱ ፥ ልቤ ፡ ጽኑ ፡ ነው ፤
እቀኛለሁ ፡ በክብሬም ፡ እዘምራለሁ ።
፪፤ በገና ፡ ሆይ ፥ ተነሥ ፥ መሰንቆም ፤
እኔም ፡ ማልጄ ፡ እነሣለሁ ።
፫፤ አቤቱ ፥ በአሕዛብ ፡ መከከል ፡ አመሰግንሃለሁ ፥
በወገኖችም ፡ መከከል ፡ እዘምርልሃለሁ ፤
፬፤ ምሕረትህ ፡ በሰማይ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ናትና ፥
እውነትህም ፡ እስከ ፡ ደመናት ፡ ድረስ ፡ ነውና ።
፭፤ አቤቱ ፥ በሰማያት ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በል ፥
ክብርህም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ትሁን ።
፮፤ ወዳጆችህ ፡ ይድኑ ፡ ዘንድ ፡
በቀኝህ ፡ አድን ፡ አድምጠኝም ።
፯፤ እግዚአብሔር ፡ በቅድስናው ፡ ተናገረ ፡—
ደስ ፡ ይለኛል ፥ ሴኬምንም ፡ እከፈላለሁ ፥
የሱኮትንም ፡ ሸለቆ ፡ እሰፍራለሁ ።
፰፤ ገለዓድ ፡ የእኔ ፡ ነው ፡ ምናሴም ፡ የእኔ ፡ ነው ፤
ኤፍሬም ፡ የራሴ ፡ መጠጊያ ፡ ነው ።
ይሁዳ ፡ ንጉሤ ፡ ነው ፤
፱፤ ሞዓብ ፡ መታጠቢያዬ ፡ ነው ፥
በኤዶምያስ ፡ ላይም ፡ ጫማዬን ፡ እዘረጋለሁ ፤
ፍልስጥኤም ፡ ይገዙልኛል ።
፲፤ ወደ ፡ ጽኑ ፡ ከተማ ፡ ማን ፡ ይወስደኛል ?
ማንስ ፡ እስከ ፡ ኤዶምያስ ፡ ይመራኛል ?
፲፩፤ አቤቱ ፥ የጣልኸን ፡ አንተ ፡ አይደለህምን ?
አምላክ ፡ ሆይ ፥ ከሠራዊታችን ፡ ጋር ፡ አትወ
ጣም ።
፲፪፤ በመከራችን ፡ ረድኤትን ፡ ስጠን ፤
የሰውም ፡ ማዳን ፡ ከንቱ ፡ ነው ።
፲፫፤ በእግዚአብሔር ፡ ኃይልን ፡ እናደርጋለን ፤
እርሱም ፡ የሚያስጨንቁንን ፡ ያዋርዳቸዋል ።

## መዝሙር ፡ ፻፰ ። (፻፱)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አምላክ ፡ ሆይ ፥ ምስጋናዬን ፡ ዝም ፡ አትበል ፥
፪፤ የኃጢአተኛ ፡ አፍና ፡ የተንኰለኛ ፡ አፍ ፡ በላዬ ፡
ተላቅቀውብኛልና ፤
በሽንገላ ፡ አንደበትም ፡ በላዬ ፡ ተናገሩ ፤
፫፤ በጥል ፡ ቃል ፡ ከበቡኝ ፥ በከንቱም ፡ ተሰለፉብኝ ።
፬፤ በወደድኋቸው ፡ ፋንታ ፡ አጣሉኝ ፥ እኔ ፡ ግን ፡
እጸልያለሁ ።
፭፤ በመልካም ፡ ፋንታ ፡ ክፉን ፥
በወደድኋቸውም ፡ ፋንታ ፡ ጠላትነትን ፡ መለሱ
ልኝ ።

፮፤ በላዩ ፡ ኃጢአተኛን ፡ ሹም ፤
ሰይጣንም ፡ በቀኙ ፡ ይቁም ።
፯፤ በተምዋገተም ፡ ጊዜ ፡ ተረትቶ ፡ ይውጣ ፤
ጸሎቱም ፡ ኃጢአት ፡ ትሁንበት ።
፰፤ ዘመናቱም ፡ ጥቂት ፡ ይሁኑ ፤
ሹመቱንም ፡ ሌላ ፡ ይውሰድ ።
፱፤ ልጆቹም ፡ ድሀ ፡ አደግ ፡ ይሁኑ ፥
ሚስቱም ፡ መበለት ፡ ትሁን ።
፲፤ ልጆቹም ፡ ተናውጠው ፡ ይቅበዝበዙ ፡ ይለም
ኑም ፥
ከስፍራቸውም ፡ ይባረሩ ።
፲፩፤ ባለዕዳም ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ይበርብረው ፥
እንግዶችም ፡ ድካሙን ፡ ሁሉ ፡ ይበዝብዙት ።
፲፪፤ የሚያግዘውንም ፡ አያግኝ ፤
ለድሀ ፡ አደግ ፡ ልጆቹም ፡ የሚራራ ፡ አይኑር ።
፲፫፤ ልጆቹ ፡ ይጥፉ ፤
በአንድ ፡ ትውልድ ፡ ስሙ ፡ ይደምሰስ ።
፲፬፤ የአባቶቹ ፡ ኃጢአት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ትታሰብ ፤
የእናቱም ፡ ኃጢአት ፡ አትደምሰስ ።
፲፭፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሁልጊዜ ፡ ይኑሩ ፤
መታሰቢያቸው ፡ ከምድር ፡ ይጥፋ ።
፲፮፤ ምሕረትን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ አላሰበምና ፡
ችግረኛንና ፡ ምስኪንን ፡
ልቡ ፡ የተሰበረውንም ፡ ሰው ፡ ይገድል ፡ ዘንድ ፡
አሳደደ ።
፲፯፤ መርገምን ፡ ወደደ ፡ ወደ ፡ እርሱም ፡ መጣች ፤
በረከትንም ፡ አልመረጠም ፡ ከእርሱም ፡ ራቀች ።
፲፰፤ መርገምን ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ለበሳት ፥
እንደ ፡ ውኃም ፡ ወደ ፡ አንጀቱ ፥
እንደ ፡ ቅባትም ፡ ወደ ፡ አጥንቱ ፡ ገባች ።
፲፱፤ እንደሚለብሰው ፡ ልብስ ፥
ሁልጊዜም ፡ እንደሚታጠቀው ፡ ትጥቅ ፡ ይሁ
ነው ።
፳፤ ይህ ፡ ሥራ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ በሚያጣ
ሉኝ ፡
በነፍሴም ፡ ላይ ፡ ክፉን ፡ በሚናገሩ ፡ ነው ።
፳፩፤ አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፥ ስለ ፡ ስምህ ፡ ምሕ
ረትህን ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ አድርግ ፤
ምሕረትህ ፡ መልካም ፡ ናትና ፡ አድነኝ ።
፳፪፤ እኔ ፡ ችግረኛ ፡ ምስኪንም ፡ ነኝና ፥
ልቤም ፡ በውስጤ ፡ ደነገጠብኝ ።
፳፫፤ እንዳለፈ ፡ ጥላ ፡ አለቅሁ ፥
እንደ ፡ አንበጣም ፡ እረገፍሁ ።
፳፬፤ ጕልበቶቼ ፡ በጾም ፡ ደከሙ ፤
ሥጋዬም ፡ ቅቤ ፡ በማጣት ፡ ከሳ ።
፳፭፤ እኔም ፡ በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ለነውር ፡ ሆንሁ ፤
ባዩኝ ፡ ጊዜ ፡ ራሳቸውን ፡ ነቀነቁ ።
፳፮፤ አቤቱ ፡ አምላኬ ፥ እርዳኝ ፥
እንደ ፡ ምሕረትህም ፡ አድነኝ ።
፳፯፤ አቤቱ ፥ እጅህ ፡ ይህች ፡ እንደ ፡ ሆነች ፥
አንተም ፡ ይህችን ፡ እንዳደረግህ ፡ ይወቁ ።
፳፰፤ እነርሱ ፡ ይራገሙ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ባርክ ፤
በእኔ ፡ ላይ ፡ የሚነሡ ፡ ይፈሩ ፥

በሪያህ ፡ ግን ፡ ደስ ፡ ይበለው ።
፳፱፤ የሚያጣሉኝ ፡ እፍረትን ፡ ይልበሱ ፤
እፍረታቸውን ፡ እንደ ፡ መጐናጸፊያ ፡ ይልበሱ
አት ።
፴፤ እግዚአብሔርን ፡ በአፌ ፡ እጅግ ፡ አመሰግነዋ
ለሁ ።
በብዙዎችም ፡ መካከል ፡ አከብረዋለሁ ፤
፴፩፤ ነፍሱን ፡ ከሚያሳድዱአት ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡
በድሀ ፡ ቀኝ ፡ ቆሞአልና ።

## መዝሙር ፡ ~~፻፱~~ ። (፻፲)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ ጌታዬን ፡— ጠላቶችህን ፡ ለእ
ግርህ ፡ መቀመጫ ፡ እስከደርግልህ ፡ ድረስ ፡
በቀኜ ፡ ተቀመጥ ፡ አለው ።
፪፤ እግዚአብሔር ፡ የኃይልን ፡ በትር ፡ ከጽዮን ፡
ይልክልሃል ፤
በጠላቶችህም ፡ መካከል ፡ ግዛ ።
፫፤ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ቀድሞ ፡ በኃይልህ ፡ ቀን ÷
በቅዱሳን ፡ ብርሃን ÷
ከአጥቢያ ፡ ኮከብ ፡ አስቀድሞ ፡ ከሆድ ፡ ወለድ
ሁህ ።
፬፤ እንደ ፡ መልከ ፡ ጼዴቅ ፡ ሥርዓት ፡
አንተ ፡ ለዘላለም ፡ ካህን ፡ ነህ ፡ ብሎ ÷
እግዚአብሔር ፡ ማለ ፡ አይጸጸትም ።
፭፤ እግዚአብሔር ፡ በቀኝህ ፡
ነገሥታትን ፡ በቍጣው ፡ ቀን ፡ ይቀጠቅጣቸዋል ።
፮፤ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ይፈርዳል ÷
ሬሳዎችንም ፡ ያበዛል ፤
በሰፊ ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ ራሶችን ፡ ይቀጠቅጣል ።
፯፤ በመንገድ ፡ ከፈሳሽ ፡ ውኃ ፡ ይጠጣል ፤
ስለዚህ ፡ ራስ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።

## መዝሙር ፡ ~~፻፲~~ ። (፻፲፩)

፩፤ ሃሌ ፡ ሉያ ።
አቤቱ ÷ በቅኖች ፡ ሸንጎ ፡ በጉባኤም ፡
በፍጹም ፡ ልቤ ፡ አመሰግንሃለሁ ።
፪፤ የእግዚአብሔር ፡ ሥራ ፡ ታላቅ ፡ ናት ÷
ደስ ፡ በሚሰኙበት ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ የተፈለገች ፡
ናት ።
፫፤ ሥራው ፡ ምስጋናና ፡ ግርማ ፡ ነው ፤
ጽድቁም ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ።
፬፤ ለተአምራቱ ፡ መታሰቢያን ፡ አደረገ ፤
እግዚአብሔር ፡ መሓሪና ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ ነው ።
፭፤ ለሚፈሩት ፡ ምግብን ፡ ሰጣቸው ፤
ኪዳኑንም ፡ ለዘላለም ፡ ያስባል ።
፮፤ የአሕዛብን ፡ ርስት ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡
ለሕዝቡ ፡ የሥራውን ፡ ብርታት ፡ አሳየ ።
፯፤ የእጆቹ ፡ ሥራ ፡ እውነትና ፡ ፍርድ ፡ ነው ፤
ትእዛዙም ፡ ሁሉ ፡ የታመነ ፡ ነው ÷
፰፤ ለዘላለምም ፡ የጸና ፡ ነው ÷
በእውነትና ፡ በቅንም ፡ የተሠራ ፡ ነው ።
፱፤ መድኃኒትንም ፡ ለሕዝቡ ፡ ሰደደ ÷
ኪዳኑንም ፡ ለዘላለም ፡ አዘዘ ፤
ስሙ ፡ የተቀደሰና ፡ የተፈራ ፡ ነው ።
፲፤ የጥበብ ፡ መጀመሪያ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍ
ራት ፡ ነው ÷
ለሚያደርጓትም ፡ ሁሉ ፡ ደኅና ፡ ማስተዋል ፡
አላቸው ፤
ምስጋናውም ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ።

## መዝሙር ፡ ~~፻፲፩~~ ። (፻፲፪)

፩፤ ሃሌ ፡ ሉያ ።
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ÷
ትእዛዙንም ፡ እጅግ ፡ የሚወድድ ፡ ሰው ፡ ምስ
ጉን ፡ ነው ።
፪፤ ዘሩ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ኃያል ፡ ይሆናል ፤
የቅኖች ፡ ትውልድ ፡ ትባረካለች ።
፫፤ ክብርና ፡ ባለጠግነት ፡ በቤቱ ፡ ነው ÷
ጽድቁም ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ።
፬፤ ለቅኖች ፡ ብርሃን ፡ በጨለማ ፡ ወጣ ፤
መሓሪና ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ ጻድቅም ፡ ነው ።
፭፤ ቸር ፡ ሰው ፡ ይራራል ፡ ያበድራልም ÷
በፍርድም ፡ ነገሩን ፡ ይፈጽማል ።
፮፤ ለዘላለም ፡ አይናወጥም ፤
የጻድቅ ፡ መታሰቢያ ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ።
፯፤ ከክፉ ፡ ነገር ፡ አይፈራም ፤
በእግዚአብሔር ፡ ለመታመን ፡ ልቡ ፡ የጸና ፡
ነው ።
፰፤ በጠላቶቹ ፡ ላይ ፡ እስኪያይ ፡ ድረስ ፡
ልቡ ፡ ጽኑ ፡ ነው ÷ አይፈራም ።
፱፤ በተነ ፡ ለችግረኞችም ፡ ሰጠ ፤
ጽድቁ ፡ ለዘላለም ፡ ዓለም ፡ ይኖራል ፤
ቀንዱ ፡ በክብር ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
፲፤ ኃጢአተኛም ፡ አይቶ ፡ ይቈጣል ÷
ጥርሱንም ፡ ያፋጫል ÷ ይቀልጣልም ፤
የኃጢአተኞችም ፡ ምኞት ፡ ትጠፋለች ።

## መዝሙር ፡ ~~፻፲፪~~ ። (፻፲፫)

፩፤ ሃሌ ፡ ሉያ ።
የእግዚአብሔር ፡ ባሪያዎች ፡ ሆይ ÷ አመስግ
ኑት ÷
የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ አመስግኑ ።
፪፤ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ቡሩክ ፡ ይሁን ።
፫፤ ከፀሐይ ፡ መውጫ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ መግቢያው ፡
ድረስ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ይመስገን ።
፬፤ እግዚአብሔር ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከፍ
ተኛ ፡ ነው ÷
ክብሩም ፡ ከሰማያት ፡ በላይ ፡ ነው ።
፭፤ እንደ ፡ አምላካችን ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ማን ፡ ነው ?
በላይ ፡ የሚኖር ፤
፮፤ በሰማይና ፡ በምድር ፡ የተዋረዱትን ፡ የሚያይ ፤
፯፤፰፤ ከአለቆች ፡ ጋር ፡ ከሕዝቡም ፡ አለቆች ፡ ጋር ፡
ያኖረው ፡ ዘንድ ፡
ችግረኛን ፡ ከመሬት ፡ የሚያነሣ ÷

ምስኪኑንም ፡ ከፋንድያ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ የሚያደ
ርግ ፤

፱፤ መካኒቱን ፡ በቤት ፡ የሚያኖራት ÷
ደስ ፡ የተሰኘችም ፡ የልጆች ፡ እናት ፡ የሚያደ
ርጋት ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

## መዝሙር ፡ ፻፲፫ ። (፻፲፬)

ሃሌ ፡ ሉያ ።

፩፤ እስራኤል ፡ ከግብጽ ÷
የያዕቆብም ፡ ቤት ፡ ከእንግዳ ፡ ሕዝብ ፡ በወጣ ፡
ጊዜ ÷

፪፤ ይሁዳ ፡ መቅደሱ ÷
እስራኤልም ፡ ግዛቱ ፡ ሆነ ።

፫፤ ባሕር ፡ አየች ፡ ሸሸችም ÷
ዮርዳኖስም ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ ተመለሰ ።

፬፤ ተራሮች ፡ እንደ ፡ ኮርማዎች ÷
ኮረብቶችም ፡ እንደ ፡ ጠቦቶች ፡ ዘለሉ ።

፭፤ አንቺ ፡ ባሕር ፡ የሸሸሽ ÷
አንቺም ፡ ዮርዳኖስ ፡ ወደ ፡ ኋላሽ ፡ የተመለ
ስሽ ÷ ምን ፡ ሆናችኋል ?

፮፤ እናንተም ፡ ተራሮች ÷ እንደ ፡ ኮርማዎች ÷
ኮረብቶችስ ÷ እንደ ፡ ጠቦቶች ፡ ለምን ፡ ዘለላ
ችሁ ?

፯፤ ከያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ፊት ÷
ከጌታ ፡ ፊት ፡ ምድር ፡ ተናወጠች ፤

፰፤ ድንጋዩን ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ መቆሚያ ÷
ጭንጫውንም ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ምንጭ ፡ ከለወጠ ።

(መዝሙር ፡ ፻፲፭ ፡ በዕብራይስጥ ፡)

፱፤(፩) ለእኛ ፡ አይደለም ÷ አቤቱ ÷ ለእኛ ፡ አይደለም ÷
ነገር ፡ ግን ፡ ለስምህ ፡
ስለ ፡ ምሕረትህ ፡ ስለ ፡ እውነትህም ፡ ምስጋናን ፡
ስጥ ።

፲፤(፪) አሕዛብ ፡— አምላካቸው ፡ ወዴት ፡ ነው ? አይ
በሉ ።

፲፩፤(፫) አምላካችንስ ፡ በላይ ፡ በሰማይ ፡ ነው ፤
በሰማይም ፡ በምድርም ፡
የፈቀደውን ፡ ሁሉ ፡ አደረገ ።

፲፪፤(፬) የአሕዛብ ፡ ጣዖታቶች ፡ የወርቅና ፡ የብር ÷
የሰው ፡ እጅ ፡ ሥራ ፡ ናቸው ።

፲፫፤(፭) አፍ ፡ አላቸው ፡ አይናገሩም ፤
ዓይን ፡ አላቸው ፡ አያዩም ፤

፲፬፤(፮) ጆሮ ፡ አላቸው ፡ አይሰሙም ፤
አፍንጫ ፡ አላቸው ፡ አያሸቱም ፤

፲፭፤(፯) እጅ ፡ አላቸው ፡ አይዳስሱም ፤
እግር ፡ አላቸው ፡ አይሄዱም ፤
በጉሮሮአቸውም ፡ አይናገሩም ።

፲፮፤(፰) የሚሠሩአቸውም ፡
የሚያምኑባቸውም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ እነርሱ ፡
ይሁኑ ።

፲፯፤(፱) የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ በእግዚአብሔር ፡
ታመኑ ፤
ረድኤታቸውና ፡ መታመኛቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።

፲፰፤(፲) የአሮን ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ በእግዚአብሔር ፡ ታመኑ ፤
ረድኤታቸውና ፡ መታመኛቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።

፲፱፤(፲፩) እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩ ፡ ሆይ ÷ በእግዚአ
ብሔር ፡ ታመኑ ፤
ረድኤታቸውና ፡ መታመኛቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።

፳፤(፲፪) እግዚአብሔር ፡ አሰበን ፡ ይባርከንማል ፤
የእስራኤልን ፡ ቤት ፡ ይባርካል ÷ የአሮንንም ፡
ቤት ፡ ይባርካል ።

፳፩፤(፲፫) እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩትን ÷
ትንንሾችንና ፡ ትልልቆችን ፡ ይባርካል ።

፳፪፤(፲፬) እግዚአብሔር ፡ በላያችሁ ÷
በላያችሁና ፡ በልጆቻችሁ ፡ ላይ ፡ ይጨምር ።

፳፫፤(፲፭) እናንተ ፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ ለሠራ ፡ ለእግዚ
አብሔር ፡ የተባረካችሁ ፡ ናችሁ ።

፳፬፤(፲፮) የሰማያት ፡ ሰማይ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ነው ፤
ምድርን ፡ ግን ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ሰጣት ።

፳፭፤(፲፯) አቤቱ ÷ ሙታን ፡ የሚያመሰግኑህ ፡ አይደሉም ÷
ወደ ፡ ሲኦልም ፡ የሚወርዱ ፡ ሁሉ ፤

፳፮፤(፲፰) እኛ ፡ ሕያዋን ፡ ግን ፡ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ዘላለም ፡
እግዚአብሔርን ፡ እንባርካለን ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

## መዝሙር ፡ ፻፲፬ ። (፻፲፮)

ሃሌ ፡ ሉያ ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ የልመናዬን ፡ ድምፅ ፡ ሰምቶአ
ልና ፡ ወደድሁት ።

፪፤ ጆሮውን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አዘንብሎአልና ፡
በዘመኔ ፡ ሁሉ ፡ እጠራዋለሁ ።

፫፤ የሞት ፡ ጣር ፡ ያዘኝ ÷ የሲኦልም ፡ ሕማም ፡ አገ
ኘኝ ፤
ጭንቀትንና ፡ መከራን ፡ አገኘሁ ።

፬፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ ጠራሁ ፡—
አቤቱ ÷ ነፍሴን ፡ አድናት ።

፭፤ እግዚአብሔር ፡ መሐሪና ፡ ጻድቅ ፡ ነው ÷
አምላካችንም ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ ነው ።

፮፤ እግዚአብሔር ፡ ሕፃናትን ፡ ይጠብቃል ፤
ተቸገርሁ ፡ እርሱም ፡ አዳነኝ ።

፯፤ ነፍሴ ፡ ሆይ ÷ ወደ ፡ ዕረፍትሽ ፡ ተመለሺ ÷
እግዚአብሔር ፡ መልካም ፡ አድርጎልሻልና ፤

፰፤ ነፍሴን ፡ ከሞት ÷ ዓይኔንም ፡ ከእንባ ÷
እግሬንም ፡ ከመሰናከል ፡ አድኖአልና ።

፱፤ በሕያዋን ፡ አገር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እሄ
ዳለሁ ።

## መዝሙር ፡ ፻፲፭ ። (፻፲፮)

፩(፲) አመንሁ ፡ ስለዚህም ፡ ተናገርሁ ፤
እኔም ፡ እጅግ ፡ ተቸገርሁ ።

፪(፲፩) እኔም ፡ ከድንጋጤዬ ፡ የተነሣ ፡— ሰው ፡ ሁሉ ፡
ሐሰተኛ ፡ ነው ፡ አልሁ ።

፫(፲፪) ስላደረገልኝ ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምንን ፡
እመልሳለሁ ?

፬(፲፫) የመድኃኒትን ፡ ጽዋ ፡ እቀበላለሁ ÷
የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ እጠራለሁ ።

(፲፬) በሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ስእለቴን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እፈጽማለሁ ።
(፲፭) የቅዱሳኑ ፡ ሞት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የከበረ ፡ ነው ።
(፲፮) አቤቱ ÷ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ነኝ ÷
ባሪያህ ፡ ነኝ ÷ የሴት ፡ ባሪያህም ፡ ልጅ ፡ ነኝ ፤
ሰንሰለቴን ፡ ሰበርህ ።
(፲፯) ለአንተ ፡ የምስጋና ፡ መሥዋዕትን ፡ እሠዋለሁ ÷
የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ እጠራለሁ ።
(፲፰) በሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ስእለቴን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እፈጽማለሁ ÷
(፲፱) በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አደባባይ ÷ ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ÷ በመካከልሽም ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

## መዝሙር ፡ ፻፲፮ ። (፻፲፯)

ሃሌ ፡ ሉያ ።

፩ ፤ አሕዛብ ፡ ሁላችሁ ÷ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑት ÷
ወገኖችም ፡ ሁሉ ፡ ያመስግኑት ፤
፪ ፤ ምሕረቱ ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ ጸንታለችና ፤
የእግዚአብሔርም ፡ እውነት ፡ ለዘላለም ፡ ትኖራለች ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

## መዝሙር ፡ ፻፲፯ ። (፻፲፰)

ሃሌ ፡ ሉያ ።

፩ ፤ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ÷ ቸር ፡ ነውና ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ናትና ።
፪ ፤ ቸር ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡
የእስራኤል ፡ ቤት ፡ አሁን ፡ ይንገሩ ።
፫ ፤ ቸር ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡
የአሮን ፡ ቤት ፡ አሁን ፡ ይንገሩ ።
፬ ፤ ቸር ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ሁሉ ፡ አሁን ፡ ይንገሩ ።
፭ ፤ በተጨነቅሁ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠራሁት ፤
ሰማኝ ፡ አሰፋልኝም ።
፮ ፤ እግዚአብሔር ፡ ረዳቴ ፡ ነው ÷ አልፈራም ፤ ሰው ፡ ምን ፡ ያደርገኛል ?
፯ ፤ እግዚአብሔር ፡ ረዳቴ ፡ ነው ÷ እኔም ፡ በጠላቶቼ ፡ ላይ ፡ እያለሁ ።
፰ ፤ በሰው ፡ ከመታመን ፡ ይልቅ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መታመን ፡ ይሻላል ።
፱ ፤ በገዢች ፡ ተስፋ ፡ ከማድረግ ፡ ይልቅ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ተስፋ ፡ ማድረግ ፡ ይሻላል ።
፲ ፤ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ከበቡኝ ÷
በእግዚአብሔርም ፡ ስም ፡ አሸነፍኋቸው ፤
፲፩ ፤ መከበቡንስ ፡ ከበቡኝ ÷
በእግዚአብሔርም ፡ ስም ፡ አሸነፍኋቸው ፤
፲፪ ፤ ንብ ፡ ማርን ፡ እንዲከብብ ፡ ከበቡኝ ÷
እሳትም ፡ በእሾህ ፡ ውስጥ ፡ እንዲነድድ ፡ ነደዱ ÷
በእግዚአብሔርም ፡ ስም ፡ አሸነፍኋቸው ።
፲፫ ፤ ገፉኝ ÷ ለመውደቅም ፡ ተንገደገድሁ ፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ አገዘኝ ።
፲፬ ፤ ኃይሌም ፡ ዝማሬዬም ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ÷
እርሱም ፡ መድኃኒት ፡ ሆነልኝ ።
፲፭ ፤ የእልልታና ፡ የመድኃኒት ፡ ድምፅ ፡ በጻድቃን ፡ ድንኳን ፡ ነው ፤
የእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ኃይልን ፡ አደረገች ።
፲፮ ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገችኝ ፤
የእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ኃይልን ፡ አደረገች ።
፲፯ ፤ አልሞትም ፡ በሕይወት ፡ እኖራለሁ ፡ እንጂ ÷
የእግዚአብሔርንም ፡ ሥራ ፡ እናገራለሁ ።
፲፰ ፤ መገሠጽስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ገሠጸኝ ፤
ለሞት ፡ ግን ፡ አልሰጠኝም ።
፲፱ ፤ የጽድቅን ፡ ደጆች ፡ ክፈቱልኝ ፤
ወደ ፡ እነርሱ ፡ ገብቼ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግናለሁ ።
፳ ፤ ይህች ፡ የእግዚአብሔር ፡ ደጅ ፡ ናት ፤
ወደ ፡ እርስዋ ፡ ጻድቃን ፡ ይገባሉ ።
፳፩ ፤ ሰምተኸኛልና ÷
መድኃኒትም ፡ ሆነኸኛልና ፡ አመሰግንሃለሁ ።
፳፪ ፤ ግንበኞች ፡ የናቁት ፡ ድንጋይ ÷
እርሱ ፡ የማዕዘን ፡ ራስ ፡ ሆነ ፤
፳፫ ፤ ይህች ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ሆነች ÷
ለዓይናችንም ፡ ድንቅ ፡ ናት ።
፳፬ ፤ እግዚአብሔር ፡ የሠራት ፡ ቀን ፡ ይህች ፡ ናት ፤
ሐሤትን ፡ እናድርግ ÷ በእርስዋም ፡ ደስ ፡ ይበለን ።
፳፭ ፤ አቤቱ ÷ እባክህ ÷ አሁን ፡ አድን ፤
አቤቱ ÷ እባክህ ÷ አሁን ፡ አቅና ።
፳፮ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የሚመጣ ፡ ቡሩክ ፡ ነው ፤
ከእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ መረቅናችሁ ።
፳፯ ፤ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ነው ÷ ለእኛም ፡ በራልን ፤
እስከ ፡ መሠዊያው ፡ ቀንዶች ፡ ድረስ ፡
የበዓሉን ፡ መሥዋዕት ፡ በገመድ ፡ እሰሩት ።
፳፰ ፤ አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነህ ፡ አመሰግንህማለሁ ።
አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነህ ÷ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርግሃለሁ ፤
ሰምተኸኛልና ÷
መድኃኒትም ፡ ሆነኸኛልና ፡ አመሰግንሃለሁ ።
፳፱ ፤ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ÷ ቸር ፡ ነውና ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ናትና ።

## መዝሙር ፡ ፻፲፰ ። (፻፲፱)

አሌፍ ።

፩ ፤ በመንገዳቸው ፡ ንጹሐን ፡ የሆኑ ÷
በእግዚአብሔርም ፡ ሕግ ፡ የሚሄዱ ፡ ምስጉኖች ፡ ናቸው ።
፪ ፤ ምስክሩን ፡ የሚፈልጉ ÷
በፍጹም ፡ ልብ ፡ የሚሹት ፡ ምስጉኖች ፡ ናቸው ፤
፫ ፤ ዓመፅንም ፡ አያደርጉም ÷ በመንገዶቹም ፡ ይሄዳሉ ።
፬ ፤ ትእዛዛትህን ፡ እጅግ ፡ እንጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ አንተ ፡

አዘዝህ ።
፭፤ ሥርዓትህን ፡ ለመጠበቅ ፡
መንገዶቼ ፡ ይቀኑ ፡ ዘንድ ፡ እወድድ ፡ ነበር ።
፮፤ ትእዛዝህን ፡ ሁሉ ፡ ስመለከት ፡
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አላፍርም ።
፯፤ አቤቱ ፥ የጽድቅህን ፡ ፍርድ ፡ ስማር ፡
በቅን ፡ ልብ ፡ አመሰግንሃለሁ ።
፰፤ ሥርዓትህን ፡ እጠብቃለሁ ፤
በፍጹም ፡ አትጣለኝ ።

ቤት ።

፱፤ ጕልማሳ ፡ መንገዱን ፡ በምን ፡ ያነጻል ?
ቃልህን ፡ በመጠበቅ ፡ ነው ።
፲፤ በፍጹም ፡ ልቤ ፡ ፈለግሁህ ፥
ከትእዛዝህ ፡ አታርቀኝ ።
፲፩፤ አንተን ፡ እንዳልበድል ፥
ቃልህን ፡ በልቤ ፡ ሰወርሁ ።
፲፪፤ አቤቱ ፥ አንተ ፡ ቡሩክ ፡ ነህ ፤
ሥርዓትህን ፡ አስተምረኝ ።
፲፫፤ የአፍህን ፡ ፍርድ ፡ ሁሉ ፡ በከንፈሬ ፡ ነገርሁ ።
፲፬፤ እንደ ፡ ብልጥግና ፡ ሁሉ ፡
በምስክርህ ፡ መንገድ ፡ ደስ ፡ አለኝ ።
፲፭፤ ትእዛዝህን ፡ አሰላስላለሁ ፥
መንገድህንም ፡ እፈልጋለሁ ።
፲፮፤ በትእዛዝህ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፤
ቃልህንም ፡ አልረሳም ።

ጋሜል ።

፲፯፤ ለባሪያህ ፡ መልካም ፡ አድርግ ፡
ሕያው ፡ እንድሆን ፥ ቃልህንም ፡ እንድጠብቅ ።
፲፰፤ ዓይኖቼን ፡ ክፈት ፥
ከሕግህም ፡ ተአምራትህን ፡ አያለሁ ።
፲፱፤ እኔ ፡ በምድር ፡ እንግዳ ፡ ነኝ ፤
ትእዛዛትህን ፡ ከእኔ ፡ አትሰውር ።
፳፤ ነፍሴ ፡ ሁልጊዜ ፡ ፍርድህን ፡ እጅግ ፡ ናፈቀች ።
፳፩፤ ከትእዛዛትህ ፡ የሳቱትን ፡ ትዕቢተኞችንና ፡ ርጉ
ማንን ፡ ዘለፍህ ።
፳፪፤ ምስክርህን ፡ ፈልጌአለሁና ፡
ስድብንና ፡ ነውርን ፡ ከእኔ ፡ አርቅ ።
፳፫፤ አለቆች ፡ ደግሞ ፡ ተቀምጠው ፡ እኔን ፡ አሙኝ ፤
ባሪያህ ፡ ግን ፡ ሕግህን ፡ ያሰላስል ፡ ነበር ።
፳፬፤ ምስክርህም ፡ ተድላዬ ፡ ነው ፥
ሥርዓትህም ፡ መከሬ ፡ ነው ።

ዳሌጥ ።

፳፭፤ ነፍሴ ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ተጠጋች ፤
እንደ ፡ ቃልህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።
፳፮፤ መንገድህን ፡ ነገርሁ ፡ ሰማኸኝም ፤
ሥርዓትህን ፡ አስተምረኝ ።
፳፯፤ የሥርዓትህን ፡ መንገድ ፡ እንዳስተውል ፡ አድ
ርገኝ ፥
ተአምራትህንም ፡ አሰላስላለሁ ።
፳፰፤ ከኀዘን ፡ የተነሣ ፡ ነፍሴ ፡ አንቀላፋች ፤
በቃልህ ፡ አጠንክረኝ ።
፳፱፤ የዓመፅን ፡ መንገድ ፡ ከእኔ ፡ አርቅ ፥
በሕግህም ፡ ማረኝ ፤
፴፤ የእውነትህን ፡ መንገድ ፡ መረጥሁ ፥
ፍርድህንም ፡ አልረሳሁም ።
፴፩፤ አቤቱ ፥ ምስክርህን ፡ ተጠጋሁ ፤ አታሳፍረኝ ።
፴፪፤ ልቤን ፡ ባሰፋኸው ፡ ጊዜ ፥
በትእዛዝህ ፡ መንገድ ፡ ሮጥሁ ።

ሄ ።

፴፫፤ አቤቱ ፥ የሥርዓትህን ፡ መንገድ ፡ አስተምረኝ ፥
ሁልጊዜም ፡ እፈልገዋለሁ ።
፴፬፤ እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ፥ ሕግህንም ፡ እፈ
ልጋለሁ ፤
በፍጹም ፡ ልቤም ፡ እጠብቀዋለሁ ።
፴፭፤ እርስዋን ፡ ወድጃለሁና ፡ የትእዛዝህን ፡ መን
ገድ ፡ ምራኝ ።
፴፮፤ ልቤን ፡ ወደ ፡ ምስክርህ ፡ አዘንብል ፥
ወደ ፡ ስስትም ፡ አይሁን ።
፴፯፤ ከንቱ ፡ ነገርን ፡ እንዳያዩ ፡ ዓይኖቼን ፡ መልስ ፤
በመንገድህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።
፴፰፤ እንዲፈሩህ ፡ ባሪያህን ፡ በቃልህ ፡ አጽና ።
፴፱፤ ፍርድህ ፡ መልካም ፡ ናትና ፡
የተጠራጠርሁትን ፡ ስድብ ፡ ከእኔ ፡ አርቅ ።
፵፤ እነሆ ፥ ትእዛዝህን ፡ ናፈቅሁ ፤
በጽድቅህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።

ዋው ።

፵፩፤ አቤቱ ፥ እንደ ፡ ቃልህ ፥
ምሕረትህና ፡ መድኃኒትህ ፡ ይምጡልኝ ።
፵፪፤ በቃልህ ፡ ታምኜለሁና ፡
ለሚሰድቡኝ ፡ በነገር ፡ እመልስላቸዋለሁ ።
፵፫፤ በፍርድህም ፡ ታምኜለሁና ፡
የእውነትን ፡ ቃል ፡ ከአፌ ፡ ፈጽመህ ፡ አታርቅ ።
፵፬፤ ለዘላለም ፡ ዓለም ፡
ሁልጊዜ ፡ ሕግህን ፡ እጠብቃለሁ ።
፵፭፤ ትእዛዛትህንም ፡ ፈልጌአለሁና ፡
አስፍቼ ፡ እሄዳለሁ ።
፵፮፤ በነገሥታት ፡ ፊት ፡ ምስክርህን ፡ እናገራለሁ ፥
አላፍርምም ፤
፵፯፤ እጅግም ፡ በወደድኋቸው ፡ በትእዛዛትህ ፡ ደስ ፡
ይለኛል ።
፵፰፤ እጆቼንም ፡ ወደ ፡ ወደድኋቸው ፡ ወደ ፡ ትእዛ
ዛትህ ፡ አነሣለሁ ፤
ሥርዓትህንም ፡ አሰላስላለሁ ።

ዛይ ።

፵፱፤ ለባሪያህ ፡ ተስፋ ፡ ያስደረግኸውን ፡ ቃልህን ፡
አስብ ።
፶፤ ቃልህ ፡ ሕያው ፡ አድርጎኛልና ፡
ይህች ፡ በመከራዬ ፡ ደስ ፡ አሰኘችኝ ።
፶፩፤ ትዕቢተኞች ፡ እጅግ ፡ ዐመፁ ፤
እኔ ፡ ግን ፡ ከሕግህ ፡ አልራቅሁም ።
፶፪፤ ከጥንት ፡ የነበረውን ፡ ፍርድህን ፡ አሰብሁ ፥
አቤቱ ፥ ተጽናናሁም ።
፶፫፤ ሕግህን ፡ ከተዉ ፡ ከኃጢአተኞች ፡ የተነሣ ፡
ኀዘን ፡ ያዘኝ ።

፶፬ በእንግድነቴ ፡ አገር ፡ ሥርዓትህ ፡ መዝሙር ፡ ሆነችኝ ።
፶፭ አቤቱ ÷ በሌሊት ፡ ስምህን ፡ አሰብሁ ÷
ሕግህንም ፡ ጠበቅሁ ።
፶፮ ትእዛዛትህንም ፡ ፈልጌአለሁና ፡ ይህች ፡ ሆነችልኝ ።

ሔት ።

፶፯ እግዚአብሔር ፡ ክፍሌ ፡ ነው ፤
ሕግህን ፡ እጠብቃለሁ ፡ አልሁ ።
፶፰ በፍጹም ፡ ልቤ ፡ ወደ ፡ ፊትህ ፡ ተማለልሁ ፤
እንደ ፡ ቃልህ ፡ ማረኝ ።
፶፱ ስለ ፡ መንገዶችህ ፡ አሰብሁ ÷
እግሬንም ፡ ወደ ፡ ምስክሮችህ ፡ መለስሁ ።
፷ ትእዛዝህን ፡ ለመጠበቅ ፡ ጨከንሁ ፡ አልዘገየሁምም ።
፷፩ የኀጥኣን ፡ ገመዶች ፡ ተተበተቡብኝ ፤
ሕግህን ፡ ግን ፡ አልረሳሁም ።
፷፪ ስለ ፡ ጽድቅህ ፡ ፍርድ ÷
በእኩለ፡ሌሊት፡እመሰግንህ፡ዘንድ፡እነሣለሁ ።
፷፫ እኔ ፡ ለሚፈሩህ ፡ ሁሉ ÷
ትእዛዝህንም ፡ ለሚጠብቁ ፡ ባልንጀራ ፡ ነኝ ።
፷፬ አቤቱ ÷ ምሕረትህ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ሞላች ፤
ሥርዓትህን ፡ አስተምረኝ ።

ጤት ።

፷፭ አቤቱ ÷ እንደ ፡ ቃልህ ፡
ለባሪያህ ፡ መልካም ፡ አደረግህ ።
፷፮ በትእዛዛትህ ፡ ታምኛለሁና ፡
መልካምን፡ምክርና፡እውቀትን፡አስተምረኝ ።
፷፯ እኔ ፡ ሳልጨነቅ ፡ ሳትሁ ፤
አሁን ፡ ግን ፡ ቃልህን ፡ ጠበቅሁ ።
፷፰ አቤቱ ÷ አንተ ፡ ቸር ፡ ነህ ÷
በቸርነትህም ፡ ሥርዓትህን ፡ አስተምረኝ ።
፷፱ የትዕቢተኞች ፡ ዓመፅ ፡ በላዬ ፡ በዛ ፤
እኔ ፡ ግን ፡ በፍጹም ፡ ልቤ ፡ ትእዛዛትህን ፡ እፈልጋለሁ ።
፸ ልባቸው ፡ እንደ ፡ ወተት ፡ ረጋ ፤
እኔ ፡ ግን ፡ በሕግህ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።
፸፩ ሥርዓትህን ፡ እማር ፡ ዘንድ ፡
ያስጨነቅኸኝ ፡ መልካም ፡ ሆነልኝ ።
፸፪ ከአእላፋት ፡ ወርቅና ፡ ብር ፡ ይልቅ ፡
የአፍህ ፡ ሕግ ፡ ይሻለኛል ።

ዮድ ።

፸፫ እጆችህ ፡ ሠሩኝ ፡ አበጃጁኝም ፤
እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ÷ ትእዛዛትህንም ፡ እማራለሁ ።
፸፬ በቃልህ ፡ ታምኛለሁና ፡
የሚፈሩህ ፡ እኔን ፡ አይተው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፸፭ አቤቱ ÷ ፍርድህ ፡ ጽድቅ ፡ እንደ ፡ ሆነች ÷
በእውነትህም ፡ እንዳስቸገርኸኝ ፡ አወቅሁ ።
፸፮ ምሕረትህ ፡ ለመጽናናቴ ፡ ትሁነኝ ÷
እንደ ፡ ቃልህም ፡ ለባሪያህ ፡ ይሁነው ።
፸፯ ሕግህ ፡ ተድላዬ ፡ ናትና ፡
ቸርነትህ ፡ ትምጣልኝ ÷ በሕይወትም ፡ ልኑር ።
፸፰ ትዕቢተኞች ፡ በዓመፅ ፡ ጠምመውብኛልና ፡ ይፈሩ ፤
እኔ ፡ ግን ፡ በትእዛዝህ ፡ እጫወታለሁ ።
፸፱ የሚፈሩህና፡ምስክሮችህን፡የሚያውቁ፡ወደ፡ እኔ ፡ ይመለሱ ።
፹ እንዳላፍር ፡ ልቤ ፡ በሥርዓትህ ፡ የቀና ፡ ይሁን ።

ካፍ ።

፹፩ ነፍሴ ፡ መድኃኒትህን ፡ ናፈቀች ፤
በቃልህም ፡ ታመንሁ ።
፹፪ መቼ ፡ ታጽናናኛለህ ፡ እያልሁ ፡
ዓይኖቼ ፡ ስለ ፡ ቃልህ ፡ ፈዘዙ ።
፹፫ በጢስ ፡ እንዳለ ፡ አቁማዳ ፡ ሆኛለሁና ፤
ሥርዓትህን ፡ ግን ፡ አልረሳሁም ።
፹፬ የባሪያህ ፡ ዘመኖች ፡ ስንት ፡ ናቸው ?
በሚያሳድዱኝስ፡ላይ፡መቼ፡ትፈርድልኛለህ ?
፹፭ ኃጢአተኞች ፡ ጨዋታን ፡ ነገሩኝ ÷
አቤቱ ÷ እንደ ፡ ሕግህ ፡ ግን ፡ አይደለም ።
፹፮ ትእዛዛትህ ፡ ሁሉ ፡ እውነት ፡ ናቸው ፤
በዓመፅ ፡ አሳደዱኝ ፤ እርዳኝ ።
፹፯ ከምድር ፡ ሊያጠፉኝ ፡ ጥቂት ፡ ቀርቶአቸው ፡ ነበር ፤
እኔ ፡ ግን ፡ ትእዛዛትህን ፡ አልተውሁም ።
፹፰ እንደ ፡ ምሕረትህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ፤
የአፍህንም ፡ ምስክር ፡ እጠብቃለሁ ።

ላሜድ ።

፹፱ አቤቱ ÷ ቃልህ ፡ በሰማይ ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ።
፺ እውነትህ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ናት ፤
ምድርን፡መሠረትሃት፡እርስዋም፡ትኖራለች ።
፺፩ ሁሉም ፡ ባሪያዎችህ ፡ ናቸውና ፡
ቀኑ ፡ በትእዛዝህ ፡ ይኖራል ።
፺፪ ሕግህ ፡ ተድላዬ ፡ ባይሆን ÷
ቀድሞ ፡ በጕስቍልናዬ ፡ በጠፋሁ ፡ ነበር ።
፺፫ በእርሱ ፡ ሕያው ፡ አድርገኸኛልና ፡
ፍርድህን ፡ ለዘላለም ፡ አልረሳም ።
፺፬ እኔ ፡ የአንተ ፡ ነኝ ፤ ፍርድህን ፡ ፈልጌአለሁና ፡ አድነኝ ።
፺፭ ኃጢአተኞች ፡ ያጠፉኝ ፡ ዘንድ ፡ ጠበቁኝ ፤
ምስክርህን ፡ ግን ፡ መረመርሁ ።
፺፮ የሥራን ፡ ሁሉ ፡ ፍጻሜ ፡ አየሁ ፤
ትእዛዝህ ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ሰፊ ፡ ነው ።

ሜም ።

፺፯ አቤቱ÷ሕግህን፡እንደ፡ምን፡እጅግ፡ወደድሁ !
ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ እርሱ ፡ ትዝታዬ ፡ ነው ።
፺፰ ለዘላለም ፡ ለእኔ ፡ ነውና ፡
ትእዛዝህ ፡ ከጠላቶቼ ፡ ይልቅ ፡ አስተዋይ ፡ አደረገኝ ።
፺፱ ምስክርህ ፡ ትዝታዬ ፡ ነውና ፡
ካስተማሩኝ ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ አስተዋልሁ ።
፻ ትእዛዝህን ፡ ፈልጌአለሁና ፡
ከሽማግሌዎች ፡ ይልቅ ፡ አስተዋልሁ ።
፻፩ ቃልህን ፡ እጠብቅ ፡ ዘንድ ፡

ከክፉ ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ እግሬን ፡ ከለከልሁ ።
፻፪፡ አስተምረኸኛልና ፡ ከፍርድህ ፡ አልራቅሁም ።
፻፫፡ ቃልህ ፡ ለጕሮሮዬ ፡ ጣፋጭ ፡ ነው ፤
ከማርና ፡ ከወለላ ፡ ይልቅ ፡ ለአፌ ፡ ጣፈጠኝ ።
፻፬፡ ከትእዛዝህ ፡ የተነሣ ፡ አስተዋልሁ ፤
ስለዚህ ፡ የሐሰትን ፡ መንገድ ፡ ጠላሁ ።

ኖን ።

፻፭፡ ሕግህ ፡ ለእግሬ ፡ መብራት ፥
ለመንገዴ ፡ ብርሃን ፡ ነው ።
፻፮፡ የጽድቅህን ፡ ፍርድ ፡ እጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ማልሁ ፥
አጸናሁም ።
፻፯፡ እጅግ ፡ ተቸገርሁ ፤ አቤቱ ፥ እንደ ፡ ቃልህ ፡
ሕያው ፡ አድርገኝ ።
፻፰፡ አቤቱ ፥ ከአፌ ፡ የሚወጣውን ፡ ቃል ፡ ውደድ ፥
ፍርድህንም ፡ አስተምረኝ ።
፻፱፡ ነፍሴ ፡ ሁልጊዜ ፡ በእጅህ ፡ ውስጥ ፡ ናት ፤
ሕግህን ፡ ግን ፡ አልረሳሁም ።
፻፲፡ ኃጢአተኞች ፡ ወጥመድን ፡ ዘረጉብኝ ፤
ከትእዛዝህ ፡ ግን ፡ አልሳትሁም ።
፻፲፩፡ የልቤ ፡ ደስታ ፡ ነውና ፡
ምስክርህን ፡ ለዘላለም ፡ ወረስሁ ።
፻፲፪፡ ለዘላለም ፡ ለፍጻሜውም ፡
ትእዛዝህን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ ልቤን ፡ አዘን
በልሁ ።

ሳምኬት ።

፻፲፫፡ ዓመፀኞችን ፡ ጠላሁ ፥ ሕግህን ፡ ግን ፡ ወደድሁ ።
፻፲፬፡ አንተ ፡ ረዳቴና ፡ መጠጊያዬ ፡ ነህ ፥
በቃልህም ፡ ተማመንሁ ።
፻፲፭፡ እናንተ ፡ ኃጢአተኞች ፥ ከእኔ ፡ ራቁ ፥
የአምላኬንም ፡ ትእዛዝ ፡ ልፈልግ ።
፻፲፮፡ እንደ ፡ ቃልህ ፡ ደግፈኝ ፥ ሕያውም ፡ እሆናለሁ ፤
ከተስፋዬም ፡ አልፈር ።
፻፲፯፡ እርዳኝ ፡ እድናለሁም ፥
ሁልጊዜም ፡ ሥርዓትህን ፡ እመረምራለሁ ።
፻፲፰፡ ምኞታቸው ፡ ዓመፃ ፡ ነውና ፡
ከሥርዓትህ ፡ የሚርቁትን ፡ ሁሉ ፡ አጐሳቈልሃ
ቸው ።
፻፲፱፡ የምድርን ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ርኵ
ሰት ፡ አጠፋሃቸው ፤
ስለዚህ ፡ ምስክርህን ፡ ወደድሁ ።
፻፳፡ ሥጋዬ ፡ አንተን ፡ ከመፍራት ፡ የተነሣ ፡ ደነገጠ ፤
ከፍርድህ ፡ የተነሣ ፡ ፈርቻለሁ ።

ዔ ።

፻፳፩፡ ፍርድንና ፡ ጽድቅን ፡ ሠራሁ ፤
ለሚያስጨንቁኝ ፡ አሳልፈህ ፡ አትስጠኝ ።
፻፳፪፡ ባሪያህን ፡ በመልካም ፡ ጠብቀው ፤
ትዕቢተኞችም ፡ አይጋፉኝ ።
፻፳፫፡ ዓይኖቼ ፡ ለማዳንህ ፥
ለጽድቅህም ፡ ቃል ፡ ፈዘዙ ።
፻፳፬፡ ለባሪያህ ፡ እንደ ፡ ምሕረትህ ፡ አድርግ ፥
ሥርዓትህንም ፡ አስተምረኝ ።
፻፳፭፡ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ነኝ ፤ እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ፥
ምስክርህንም ፡ አውቃለሁ ።
፻፳፮፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሥራ ፡ ጊዜ ፡ ነው ፥
ሕግህንም ፡ ሻሩት ።
፻፳፯፡ ስለዚህ ፡ ከወርቅና ፡ ከዕንቍ ፡ ይልቅ ፡ ትእዛዝ
ህን ፡ ወደድሁ ።
፻፳፰፡ ስለዚህ ፡ ወደ ፡ ትእዛዝህ ፡ ሁሉ ፡ አቀናሁ ፥
የዓመፅንም ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ ጠላሁ ።

ፌ ።

፻፳፱፡ ምስክሮችህ ፡ ድንቆች ፡ ናቸው ፤
ስለዚህ ፡ ነፍሴ ፡ ፈለገቻቸው ።
፻፴፡ የቃልህ ፡ ፍቺ ፡ ያበራል ፥
ሕፃናትንም ፡ አስተዋዮች ፡ ያደርጋል ።
፻፴፩፡ አፌን ፡ ከፈትሁ ፥ አለከለክሁም ፤
ወደ ፡ ትእዛዝህ ፡ ናፍቄአለሁና ።
፻፴፪፡ ስምህን ፡ ለሚወድዱ ፡ እንደምታደርገው ፡
ፍርድ ፥
ወደ ፡ እኔ ፡ ተመልከት ፡ ማረኝም ።
፻፴፫፡ አካሄዴን ፡ እንደ ፡ ቃልህ ፡ አቅና ፤
ኃጢአትም ፡ ሁሉ ፡ አይግዛኝ ።
፻፴፬፡ ከሰው ፡ ግፍ ፡ አድነኝ ፤
ትእዛዝህንም ፡ እጠብቃለሁ ።
፻፴፭፡ በባሪያህ ፡ ላይ ፡ ፊትህን ፡ አብራ ፥
ሥርዓትህንም ፡ አስተምረኝ ።
፻፴፮፡ ሕግህን ፡ አልጠበቅሁምና ፡
የውኃ ፡ ፈሳሽ ፡ ከዓይኖቼ ፡ ፈሰሰ ።

ጻዴ ።

፻፴፯፡ አቤቱ ፥ አንተ ፡ ጻድቅ ፡ ነህ ፥ ፍርድህም ፡
ቅን ፡ ነው ።
፻፴፰፡ ምስክርህን ፡ በጽድቅ ፡ አዘዝህ ፥
እጅግም ፡ ቅን ፡ ነው ።
፻፴፱፡ ጠላቶቼ ፡ ቃልህን ፡ ረስተዋልና ፡
የቤትህ ፡ ቅንዓት ፡ አቀለጠኝ ።
፻፵፡ ቃልህ ፡ እጅግ ፡ የነጠረ ፡ ነው ፥
ባሪያህም ፡ ወደደው ።
፻፵፩፡ እኔ ፡ ታናሽና ፡ የተናቅሁ ፡ ነኝ ፤
ትእዛዛትህን ፡ ግን ፡ አልረሳሁም ።
፻፵፪፡ ጽድቅህ ፡ የዘላለም ፡ ጽድቅ ፡ ነው ፥
ቃልህም ፡ እውነት ፡ ነው ።
፻፵፫፡ መከራና ፡ ችግር ፡ አገኙኝ ፤
ትእዛዛትህ ፡ ግን ፡ ተድላዬ ፡ ናቸው ።
፻፵፬፡ ምስክርህ ፡ ለዘላለም ፡ ጽድቅ ፡ ነው ፤
እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ፥ በሕይወትም ፡ እኑ
ረኝ ።

ቆፍ ።

፻፵፭፡ በፍጹም ፡ ልቤ ፡ ጮኽሁ ፥ አቤቱ ፥ ስማኝ ፤
ሥርዓትህን ፡ እፈልጋለሁ ።
፻፵፮፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኽሁ ፤ አድነኝ ፥
ምስክርህንም ፡ እጠብቃለሁ ።
፻፵፯፡ ማለዳ ፡ ጮኽሁ ፤
ቃልህንም ፡ ተስፋ ፡ አድርጌአለሁ ።
፻፵፰፡ ቃልህን ፡ አስብ ፡ ዘንድ ፡
ዓይኖቼ ፡ ለመማለድ ፡ ቀደሙ ።

፻፵፱፤ አቤቱ ፥ እንደ ፡ ቸርነትህ ፡ ድምፄን ፡ ስማ ፤
እንደ ፡ ፍርድህ ፡ሕያው ፡ አድርገኝ ።
፻፶፤ በዓመፃ ፡ የሚያሳድዱኝ ፡ ቀረቡ ፥
ከሕግህም ፡ ራቁ ።
፻፶፩፤ አቤቱ ፥ አንተ ፡ ቅርብ ፡ ነህ ፥
መንገዶችህም ፡ ሁሉ ፡ ቅኖች ፡ ናቸው ።
፻፶፪፤ ከዘላለም ፡ እንደ ፡ መሠረትኸው ፡
ከቀድሞ ፡ ጀምሮ ፡ ከምስክርህ ፡ የተነሣ ፡ አወ
ቅሁ ።

ሬስ ።

፻፶፫፤ ሕግህን ፡ አልረሳሁምና ፡
ችግሬን ፡ ተመልከት ፡ አድነኝም ።
፻፶፬፤ ፍርዴን ፡ ፍረድ ፡ አድነኝም ፤
ስለ ፡ ቃልህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።
፻፶፭፤ መድኃኒት ፡ ከኃጥአን ፡ሩቅ ፡ ነው ፥
ሥርዓትህን ፡ አልፈለጉምና ።
፻፶፮፤ አቤቱ ፥ ቸርነትህ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነው ፤
እንደ ፡ ፍርድህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።
፻፶፯፤ ያሳደዱኝና ፡ ያስጨነቁኝ ፡ ብዙዎች ፡ ናቸው ፤
ከምስክር ፡ ግን ፡ ፈቀቅ ፡ አላልሁም ።
፻፶፰፤ ቃልህን ፡ አልጠበቁምና ፡
ሰነፎችን ፡ አይቼ ፡ አዘንሁ ።
፻፶፱፤ ትእዛዝህን ፡ እንደ ፡ ወደድሁ ፡ ተመልከት ፤
አቤቱ ፥ በምሕረትህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።
፻፷፤ የቃልህ ፡ መጀመሪያ ፡ እውነት ፡ ነው ፥
የጽድቅህም ፡ ፍርድ ፡ ሁሉ ፡ ለዘላለም ፡
ነው ።

ሳን ።

፻፷፩፤ ገዢዎች ፡ በከንቱ ፡ አሳደዱኝ ፤
ከቃልህ ፡ የተነሣ ፡ ግን ፡ ልቤ ፡ ደነገጠብኝ ።
፻፷፪፤ ብዙ ፡ ምርኮ ፡ እንዳገኘ ፡ በቃልህ ፡ ደስ ፡
አለኝ ።
፻፷፫፤ ዓመፃን ፡ ጠላሁ ፡ ተጸየፍሁም ፤
ሕግህን ፡ ግን ፡ ወደድሁ ።
፻፷፬፤ ስለ ፡ ጽድቅህ ፡ ፍርድ ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ በቀን ፡
አመሰግንሃለሁ ።
፻፷፭፤ ሕግህን ፡ ለሚወድዱ ፡ ብዙ ፡ ሰላም ፡ ነው ፥
ዕንቅፋትም ፡ የለባቸውም ።
፻፷፮፤ አቤቱ ፥ ማዳንህን ፡ ተስፋ ፡ አደረግሁ ፥
ትእዛዛትህንም ፡ ጠበቅሁ ።
፻፷፯፤ ነፍሴ ፡ ምስክርህን ፡ ጠበቀች ፥
እጅግም ፡ ወደደችው ።
፻፷፰፤ መንገዶቼ ፡ ሁሉ ፡ በፊትህ ፡ ናቸውና ፡
ትእዛዝህንና ፡ ምስክርህን ፡ ጠበቅሁ ።

ታው ።

፻፷፱፤ አቤቱ ፥ ጸሎቴ ፡ ወደ ፡ ፊትህ ፡ ትቅረብ ፤
እንደ ፡ ቃልህም ፡ አስተዋይ ፡ አድርገኝ ።
፻፸፤ ልመናዬ ፡ ወደ ፡ ፊትህ ፡ ትድረስ ፤
እንደ ፡ ቃልህ ፡ አድነኝ ።
፻፸፩፤ ሥርዓትህን ፡ አስተምረኸኛልና ፡
ከንፈሮቼ ፡ ምስጋናን ፡ አወጡ ።
፻፸፪፤ ትእዛዛትህ ፡ ሁሉ ፡ ጽድቅ ፡ ናቸውና ፡
አንደበቴ ፡ ቃልህን ፡ ተናገረ ።
፻፸፫፤ ትእዛዛትህን ፡ መርጫለሁና ፡
እጅህ ፡ የሚያድነኝ ፡ ይሁን ።
፻፸፬፤ አቤቱ ፥ ማዳንህን ፡ ናፈቅሁ ፤
ሕግህም ፡ ተድላዬ ፡ ነው ።
፻፸፭፤ ነፍሴ ፡ ትኑርልኝ ፡ ታመሰግንህማለች ፥
ፍርድህም ፡ ይርዳኝ ።
፻፸፮፤ እንደ ፡ ጠፋ ፡ በግ ፡ ተቅበዘበዝሁ ፤
ትእዛዛትህን ፡ አልረሳሁምና ፡ ባሪያህን ፡ ፈል
ገው ።

## መዝሙር ፡ ፻፲፱ ። (፻፳)

የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩፤ በተጨነቅሁ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ጮኽሁ ፥ ሰማኝም ።
፪፤ ከዓመፀኛ ፡ ከንፈር ፡ ከሸንጋይም ፡ አንደበት ፥
አቤቱ ፥ ነፍሴን ፡ አድናት ።
፫፤ ስለ ፡ ሸንገላ ፡ አንደበት ፡ ምንን ፡ ይሰጡሃል ?
ምንስ ፡ ይጨምሩልሃል ?
፬፤ እንደ ፡ በረሃ ፡ እንጨት ፡ ፍም ፡ የኃያላን ፡ ፍላ
ጾች ፡ የተሳሉ ፡ ናቸው ።
፭፤ መኖሪያዬ ፡ የራቀ ፡ እኔ ፡ ወዮልኝ ፤
በቄዳር ፡ ድንኳኖች ፡ አደርሁ ።
፮፤ ሰላምን ፡ ከሚጠሉ ፡ ጋር ፡
ነፍሴ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ኖረች ።
፯፤ እኔ ፡ ሰላማዊ ፡ ነኝ ፤
በተናገርኋቸው ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ በከንቱ ፡ ተሰለፉ
ብኝ ።

## መዝሙር ፡ ፻፳ ። (፻፳፩)

የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩፤ ዓይኖቼን ፡ ወደ ፡ ተራሮች ፡ አነሣሁ ፤
ረዳቴ ፡ ከወዴት ፡ ይምጣ ?
፪፤ ረዳቴ ፡ ሰማይና ፡ ምድርን ፡ ከሠራ ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
፫፤ እግርህን ፡ ለመናወጥ ፡ አይሰጠውም ፤
የሚጠብቅህም ፡ አይተኛም ።
፬፤ እነሆ ፥ እስራኤልን ፡ የሚጠብቅ ፡ አይተኛም ፡
አያንቀላፋምም ።
፭፤ እግዚአብሔር ፡ ይጠብቅሃል ፥
እግዚአብሔርም ፡ በቀኝ ፡ እጅህ ፡ በኩል ፡ ይጋ
ርድሃል ።
፮፤ ፀሐይ ፡ በቀን ፡ አያቃጥልህም ፡ ጨረቃም ፡ በሌ
ሊት ።
፯፤ እግዚአብሔር ፡ ከክፉ ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቅሃል ፥
ነፍስህንም ፡ ይጠብቃታል ።
፰፤ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡
እግዚአብሔር ፡ መውጣትህንና ፡ መግባትህን ፡
ይጠብቃል ።

## መዝሙር ፡ ፻፳፩ ። (፻፳፪)

የዳዊት ፡ የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩፤ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እንሂድ ፡ ባሉኝ ፡
ጊዜ ፡ ደስ ፡ አለኝ ።

፪ ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ÷ እግሮቻችን ፡ በአዳባባይሽ ፡ ቆሙ ።
፫ ኢየሩሳሌምስ ፡ እርስ ፡ በርስዋ ፡ እንደ ፡ ተገጠገጠች ፡ ከተማ ፡ ተሠርታለች ።
፬ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ÷ ለእስራኤል ፡ ምስክር ፡ ሊሆኑ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነገዶች ፡ ወደዚያ ፡ ይወጣሉ ።
፭ ዙፋኖች ፡ በዚያ ፡ ለፍርድ ፡ ተቀምጠዋልና ÷ የዳዊት ፡ ቤት ፡ ዙፋኖች ።
፮ ለኢየሩሳሌም ፡ ሰላምን ፡ ለምኑ ፤
አንተንም ፡ ለሚወድዱ ፡ ልማት ፡ ይሁን ።
፯ በኃይልህ ፡ ሰላም ÷
በጌጠኛ ፡ ቤትህም ፡ ልማት ፡ ይሁን ።
፰ ስለ ፡ ወንድሞቼ ፡ ስለ ፡ በልንጀሮቼም ፡—
በውስጥሽ ፡ ሰላም ፡ ይሁን ፡ አልሁ ።
፱ ስለ ፡ አምላካችን ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ላንቺ ፡ መልካምነትሽን ፡ ፈለግሁ ።

## መዝሙር ፡ ፻፳፪ ። (፻፳፫)

የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩ በሰማይ ፡ የምትኖር ፡ ሆይ ÷ ዓይኖቼን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ አነሣሁ ።
፪ እነሆ ÷ የባሪያዎች ፡ ዓይኖች ፡ ወደ ፡ ጌታቸው ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ሆኑ ÷
የባሪያይቱም ፡ ዓይን ፡ ወደ ፡ እመቤትዋ ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷
እንዲሁ ፡ እስኪምረን ፡ ድረስ ፡
ዓይናችን ፡ ወደ ፡ አምላካችን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ።
፫ ማረን ÷ አቤቱ ÷ ማረን ፤
ንቀትን ፡ እጅግ ፡ ጠግበናልና ፤
፬ የባለጠጎችን ፡ ስድብና ፡ የትዕቢተኞችን ፡ ንቀት ፡ ነፍሳችን ፡ እጅግ ፡ ጠገበች ።

## መዝሙር ፡ ፻፳፫ ። (፻፳፬)

የዳዊት ፡ የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩ እግዚአብሔር ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ባይሆን ፡ እስራኤል ፡ እንዲህ ፡ ይበል ፡—
፪ እግዚአብሔር ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ባይሆን ፡ ሰዎች ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ በተነሡ ፡ ጊዜ ÷
፫ ቍጣቸው ፡ በላያችን ፡ በነደደ ፡ ጊዜ ÷
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሕያዋን ፡ ሳለን ፡ በዋጡን ፡ ነበር ፤
፬ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ውኃ ፡ በሰጠመን ፡ ነበር ÷
በነፍሳችንም ፡ ላይ ፡ ፈሳሽ ፡ በለፈ ፡ ነበር ፤
፭ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የጐርፍ ፡ ውኃ ፡ በነፍሳችን ፡ ላይ ፡ በለፈ ፡ ነበር ።
፮ ለጥርሳቸው ፡ ንክሻ ፡ ያላደረገን ፡ እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ።
፯ ነፍሳችን ፡ እንደ ፡ ወፍ ፡ ከአዳኞች ፡ ወጥመድ ፡ አመለጠች ፤
ወጥመድ ፡ ተሰበረ ፡ እኛም ፡ አመለጥን ።
፰ ረድኤታችን ፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ በሠራ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ነው ።

## መዝሙር ፡ ፻፳፬ ። (፻፳፭)

የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩ በእግዚአብሔር ፡ የታመኑ ፡
እንደማይታወክ ፡ ለዘላለም ፡ እንደሚኖር ፡ እንደ ፡ ጽዮን ፡ ተራራ ፡ ናቸው ።
፪ ተራሮች ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ዙሪያ ፡ እንደ ፡ ሆኑ ÷
ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ ለዘላለም ፡
እግዚአብሔር ፡ በሕዝቡ ፡ ዙሪያ ፡ ነው ።
፫ ጻድቃን ፡ እጃቸውን ፡ ወደ ፡ ክፋት ፡ እንዳይዘረጉ ፡
የኀጥአን ፡ በትር ፡ በጻድቃን ፡ ዕጣ ፡ ላይ ፡ አይኖርም ።
፬ አቤቱ ÷ ለቸሮች ፡ ልባቸውም ፡ ለቀና ፡ መልካምን ፡ አድርግ ።
፭ ወደ ፡ ጠማማነት ፡ የሚመለሱትን ፡ ግን ፡
ዓመፅን ፡ ከሚሠሩት ፡ ጋር ፡ እግዚአብሔር ፡ ይወስዳቸዋል ።
ሰላም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ይሁን ።

## መዝሙር ፡ ፻፳፭ ። (፻፳፮)

የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩ እግዚአብሔር ፡ የጽዮንን ፡ ምርኮ ፡ በመለሰ ፡ ጊዜ ÷
እጅግ ፡ ደስተኞች ፡ ሆንን ።
፪ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አፋችን ፡ ደስታን ÷
አንደበታችንም ፡ ሐሤትን ፡ ሞላ ፤
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡—
እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ነገርን ፡ አደረገላቸው ፡ ተባለ ።
፫ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ነገርን ፡ አደረገልን ÷
ደስም ፡ አለን ።
፬ አቤቱ ÷ በደቡብ ፡ እንዳሉ ፡ ፈሳሾች ፡
ምርኮአችንን ፡ መልስ ።
፭ በልቅሶ ፡ የሚዘሩ ፡ በደስታ ፡ ይለቅማሉ ።
፮ በሄዱ ፡ ጊዜ ÷ ዘራቸውን ፡ ተሸክመው ፡ እያለቀሱ ፡ ተሰማሩ ፤
በተመለሱ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ነዶአቸውን ፡ ተሸክመው ፡ ደስ ፡ እያላቸው ፡ ይመጣሉ ።

## መዝሙር ፡ ፻፳፮ ። (፻፳፯)

የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩ እግዚአብሔር ፡ ቤትን ፡ ካልሠራ ÷
ሠራተኞች ፡ በከንቱ ፡ ይደክማሉ ፤
እግዚአብሔር ፡ ከተማን ፡ ካልጠበቀ ÷
ጠባቂ ፡ በከንቱ ፡ ይተጋል ።
፪ በማለዳ ፡ መገሥገሣችሁም ፡ ከንቱ ፡ ነው ።
ለወዳጆቹ ፡ እንቅልፍን ፡ በሰጠ ፡ ጊዜ ÷
እናንተ ፡ የመከራን ፡ እንጀራ ፡ የምትበሉ ÷
ከተቀመጣችሁበት ፡ ተነሡ ።
፫ እነሆ ÷ ልጆች ፡ የእግዚአብሔር ፡ ስጦታ ፡ ናቸው ÷
የሆድም ፡ ፍሬ ፡ የእርሱ ፡ ዋጋ ፡ ነው ።
፬ በኃያል ፡ እጅ ፡ እንዳሉ ፡ ፍላጾች ÷
የጐልማስነት ፡ ልጆች ፡ እንዲሁ ፡ ናቸው ።

፭ ከእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ምኞቱን ፡ የሚፈጽም ፡ ብፁዕ ፡ ሰው ፡ ነው ፤
ጠላቶቻቸውን ፡ በአደባባይ ፡ በተናገሩ ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ አያፍርም ።

## መዝሙር ፡ ፻፳፯ ። (፻፳፰)

የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩት ፡ ሁሉ ÷
በመንገዶቹም ፡ የሚሄዱ ፡ ምስጉኖች ፡ ናቸው ።
፪ የድካምህን ፡ ፍሬ ፡ ትመገባለህ ፤
ምስጉን ፡ ነህ ፡ መልካምም ፡ ይሆንልሃል ።
፫ ሚስትህ ፡ በቤትህ ፡ እልፍኝ ፡ ውስጥ ፡ እንደሚያፈራ ፡ ወይን ፡ ናት ፤
ልጆችህ ፡ በማዕድህ ፡ ዙሪያ ፡ እንደ ፡ ወይራ ፡ ቡቃያ ፡ ናቸው ።
፬ እነሆ ÷ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ይባረካል ።
፭ እግዚአብሔር ፡ ከጽዮን ፡ ይባርክህ ፤
በሕይወትህ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ÷
የኢየሩሳሌምን ፡ መልካምነትዋን ፡ ታያለህ ።
፮ የልጆችህንም ፡ ልጆች ፡ ታያለህ ።
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ሰላም ፡ ይሁን ።

## መዝሙር ፡ ፻፳፰ ። (፻፳፱)

የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩ እስራኤል ፡— ከትንሽነቴ ፡ ጀምሮ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ተሰለፉብኝ ፡ ይበል ፤
፪ ከትንሽነቴ ፡ ጀምሮ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ተሰለፉብኝ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ አላሸነፉኝም ።
፫ ኃጢአተኞች ፡ በጀርባዬ ፡ ላይ ፡ መቱኝ ÷
ኃጢአታቸውንም ፡ አስረዘሙአት ።
፬ እግዚአብሔር ፡ ጻድቅ ፡ ነው ፤
የኃጢአተኞችን ፡ አንገታቸውን ፡ ቈረጠ ።
፭ ጽዮንን ፡ የሚጠሉ ፡ ሁሉ ፡ ይፈሩ ÷
ወደ ፡ ኋላቸውም ፡ ይመለሱ ።
፮ በሰገነት ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ በቀለ ፡ ሣር ÷
ሳይነቀል ፡ እንደሚደርቅ ÷
፯ ለሚያጭደው ፡ እጁን ÷
ነዶዎቹን ፡ ለሚሰበስብ ፡ እቅፉን ፡ እንደማይሞላ ፡ ይሁኑ ።
፰ በመንገድም ፡ የሚያልፉ ፡— የእግዚአብሔር ፡ በረከት ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ይሁን ፤
በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ እንመርቃችኋለን ፡ አይሉም ።

## መዝሙር ፡ ፻፳፱ ። (፻፴)

የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ÷ አንተን ፡ ከጥልቅ ፡ ጠራሁህ ።
፪ አቤቱ ÷ ድምፄን ፡ ስማ ፤
ጆሮህ ፡ የልመናዬን ፡ ቃል ፡ የሚያደምጥ ፡ ይሁን ።
፫ አቤቱ ÷ ኃጢአትንስ ፡ ብትጠባበቅ ÷
አቤቱ ÷ ማን ፡ ይቆማል ?
፬ ይቅርታ ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ ነውና ።
፭ አቤቱ ÷ ስለ ፡ ስምህ ፡ ተስፋ ፡ አደረግሁህ ፤
ነፍሴ ፡ በሕግህ ፡ ታገሠች ።
፮ ከማለዳው ፡ ሰዓት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሌሊት ፡
ነፍሴ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታመነች ።
፯ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ምሕረት ÷
በእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ብዙ ፡ ማዳን ፡ ነውና ፡
እስራኤል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ይታመን ።
፰ እርሱም ፡ እስራኤልን ፡ ከኃጢአቱ ፡ ሁሉ ፡ ያድነዋል ።

## መዝሙር ፡ ፻፴ ። (፻፴፩)

የዳዊት ፡ መዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ÷ ልቤ ፡ አይታበይብኝ ÷
ዓይኖቼም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አይበሉብኝ ፤
ከትልልቆች ፡ ጋር ÷
ከእኔም ፡ ይበልጥ ፡ ከሚከበሩ ፡ ጋር ፡ አልሄድሁም ።
፪ ነፍሴን ፡ አሳረፍኋት ÷
የእናቱንም ፡ ጡት ፡ እንዳስተዉት ፡ ዝም ፡ አሰኘኋት ፤
ነፍሴ ፡ የእናቱን ፡ ጡት ፡ እንዳስተዉት ፡ በእኔ ፡ ውስጥ ፡ ናት ።
፫ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡
እስራኤል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ይታመን ።

## መዝሙር ፡ ፻፴፩ ። (፻፴፪)

የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ÷ ዳዊትን ፡ ገርነቱንም ፡ ሁሉ ፡ አስብ ፤
፪ ለእግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ማለ ÷
ለያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ተሳለ ፡—
፫ በእውነት ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ ድንኳን ፡ አልገባም ÷
ወደ ፡ ምንጣፌም ፡ አልጋ ፡ አልወጣም ÷
፬ ለዓይኖቼም ፡ መኝታ ፡ ለሽፋሽፍቶቼም ፡ እንቅልፍ ÷
ለጕንጮቼም ፡ ዕረፍትን ፡ አልሰጥም ÷
፭ ለእግዚአብሔር ፡ ስፍራ ÷
ለያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ማደሪያ ፡ እስካገኝ ፡ ድረስ ፡ ብሎ ።
፮ እነሆ ÷ በኤፍራታ ፡ ሰማነው ÷
በዱር ፡ ውስጥም ፡ አገኘነው ።
፯ ወደ ፡ ማደሪያዎቹ ፡ እንገባለን ፤
እግሮቹ ፡ በሚቆሙበት ፡ ስፍራ ፡ እንሰግዳለን ።
፰ አቤቱ ÷ ወደ ፡ ዕረፍትህ ፡ ተነሥ ÷
አንተና ፡ የመቅደስህ ፡ ታቦት ።
፱ ካህናቶችህ ፡ ጽድቅን ፡ ይልበሱ ÷
ቅዱሳንህም ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ።
፲ ስለ ፡ ዳዊት ፡ ስለ ፡ ባሪያህ ፡
የቀባኸውን ፡ ሰው ፡ ፊት ፡ አትመልስ ።
፲፩ እግዚአብሔር ፡ ለዳዊት ፡ በእውነት ፡ ማለ ፡ አይጸጸትምም ÷
እንዲህ ፡ ብሎ ፡— ከሆድህ ፡ ፍሬ ፡ በዙፋንህ ፡ ላይ ፡ አስቀምጣለሁ ።
፲፪ ልጆችህ ፡ ኪዳኔን ÷
ይህንም ፡ የማስተምራቸውን ፡ ምስክሬን ፡ ቢጠብቁ ÷

ልጆቻቸው ፡ ደግሞ ፡ በዙፋንህ ፡ ላይ ፡ ለዘላለም ፡
ይቀመጣሉ ።

፲፫ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጽዮንን ፡ መርጦአታልና ÷
ማደሪያውም ፡ ትሆነው ፡ ዘንድ ፡ ወድዶአታ
ልና ÷ እንዲህ ፡ ብሎ ፡—

፲፬ ፡ ይህች ፡ ለዘላለም ፡ ማረፊያዬ ፡ ናት ፤
መርጫታለሁና ፡ በዚህች ፡ አድራለሁ ።

፲፭ ፡ አሮጊቶችዋን ፡ እጅግ ፡ እባርካለሁ ÷
ድሆችዋንም ፡ እንጀራ ፡ አጠግባለሁ ።

፲፮ ፡ ካህናቶችዋንም ፡ ደኅንነትን ፡ አለብሳቸዋለሁ ÷
ቅዱሳኖችዋም ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።

፲፯ ፡ በዚያ ፡ ለዳዊት ፡ ቀንድን ፡ አበቅላለሁ ÷
ለቀባሁትም ፡ ሰው ፡ መብራትን ፡ አዘጋጃለሁ ።

፲፰ ፡ ጠላቶችንም ፡ እፍረትን ፡ አለብሳቸዋለሁ ፤
በእርሱ ፡ ግን ፡ ቅድስናዬ ፡ ያብባል ።

## መዝሙር ፡ ፻፴፪ ። (፻፴፫)

የዳዊት ፡ የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩ ፡ ወንድሞች ፡ በኅብረት ፡ ቢቀመጡ ÷
እነሆ ÷ መልካም ፡ ነው ÷ እነሆም ÷ ያማረ ፡ ነው ።

፪ ፡ ከራስ ፡ እስከ ፡ ጢም ፡ እንደሚፈስስ ÷
እስከ ፡ አሮን ፡ ጢም ÷
በልብሱ ፡ መደረቢያም ፡ እንደሚወርድ ፡ ሽቱ ፡
ነው ።

፫ ፡ በጽዮን ፡ ተራሮች ፡ እንደሚወርድ ፡ እንደ ፡
አርሞንዔም ፡ ጠል ፡ ነው ፤
በዚያ ፡ እግዚአብሔር ፡ በረከቱን ፡
ሕይወትንም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ አዝዞአልና ።

## መዝሙር ፡ ፻፴፫ ። (፻፴፬)

የመዓርግ ፡ መዝሙር ።

፩ ፡ እነሆ ÷ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩ ÷
በአምላካችን ፡ ቤት ፡ አደባባዮች ፡ የምትቆሙ ፡
እናንተ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባሪያዎች ፡ ሁላችሁ ።

፪ ፡ በሌሊት ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ውስጥ ፡ እጆቻች
ሁን ፡ አንሡ ÷
እግዚአብሔርንም ፡ ባርኩ ።

፫ ፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ የሠራ ፡ እግዚአብሔር ፡
ከጽዮን ፡ ይባርክህ ።

## መዝሙር ፡ ፻፴፬ ። (፻፴፭)

፩ ፡ ሃሌ ፡ ሉያ ።
የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ አመስግኑ ፤
እናንተ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባሪያዎች ፡ ሆይ ÷
አመስግኑት ÷

፪ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ውስጥ ÷
በአምላካችን ፡ ቤት ፡ አደባባይ ፡ የምትቆሙ ።

፫ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸር ፡ ነውና ፡ እግዚአብሔርን ፡
አመስግኑ ፤
ለስሙ ፡ ዘምሩ ÷ መልካም ፡ ነውና ፤

፬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያዕቆብን ፡ ለራሱ ÷
እስራኤልንም ፡ ለመዝገቡ ፡ መርጦታልና ፤

፭ ፡ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷
ጌታችንም ፡ ከአማልክት ፡ ሁሉ ፡ እንዲበልጥ ፡
አውቄአለሁና ።

፮ ፡ በሰማይና ፡ በምድር ፡ በባሕርና ፡ በጥልቆች ፡
ሁሉ ÷
እግዚአብሔር ፡ የወደደውን ፡ ሁሉ ፡ አደረገ ።

፯ ፡ ከምድር ፡ ዳር ፡ ደመናትን ፡ ያወጣል ፤
በዝናብ ፡ ጊዜ ፡ መብረቅን ፡ አደረገ ፤
ነፋሳትንም ፡ ከመዛግብቱ ፡ ያወጣል ።

፰ ፡ የግብጽን ፡ በኵር ፡ ልጆች ፡
ከሰው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ እንስሳ ፡ ድረስ ፡ መታ ።

፱ ፡ ግብጽ ፡ ሆይ ÷ በመካከልሽ ፡ በፈርዖንና ፡ በባሪ
ያዎቹ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡
ተአምራትንና ፡ ድንቅን ፡ ሰደደ ።

፲ ፡ ብዙ ፡ አሕዛብን ፡ መታ ÷ ብርቱዎችንም ፡ ነገሥ
ታትን ፡ ገደለ ።

፲፩ ፡ የአሞራውያንን ፡ ንጉሥ ፡ ሴዎንን ÷ የባሳንንም ፡
ንጉሥ ፡ ዐግን ÷
የከነዓንን ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ ገደለ ፤

፲፪ ፡ ምድራቸውንም ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡
ለእስራኤል ፡ ለሕዝቡ ፡ ርስት ፡ ሰጠ ።

፲፫ ፡ አቤቱ ÷ ስምህ ፡ ለዘላለም ፡ ነው ÷
ዝክርህም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ፤

፲፬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ፡ ይፈርዳልና ÷
ባሪያዎቹንም ፡ ይረዳልና ።

፲፭ ፡ የአሕዛብ ፡ ጣዖታት ፡ የብርና ፡ የወርቅ ÷
የሰው ፡ እጅ ፡ ሥራ ፡ ናቸው ።

፲፮ ፡ አፍ ፡ አላቸው ÷ አይናገሩምም ፤
ዓይን ፡ አላቸው ÷ አያዩምም ፤

፲፯ ፡ ጆሮ ፡ አላቸው ÷ አይሰሙምም ፤
እስትንፋስም ፡ በአፋቸው ፡ የለም ።

፲፰ ፡ የሚሠሩአቸው ፡ ሁሉ ፡
የሚታመኑባቸውም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ እነርሱ ፡
ይሁኑ ።

፲፱ ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ እግዚአብሔርን ፡
ባርኩት ፤
የአሮን ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩት ፤

፳ ፡ የሌዊ ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩት ፤
እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩት ፡ ሆይ ÷ እግዚአ
ብሔርን ፡ ባርኩት ።

፳፩ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሚያድር ፡ እግዚአብሔር ፡
ከጽዮን ፡ የተባረከ ፡ ነው ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

## መዝሙር ፡ ፻፴፭ ። (፻፴፮)

፩ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፤ ቸር ፡ ነውና ÷
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።

፪ ፡ የአማልክትን ፡ አምላክ ፡ አመስግኑ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።

፫ ፡ የጌቶችን ፡ ጌታ ፡ አመስግኑ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤

፬ ፡ እርሱ ፡ ብቻውን ፡ ታላቅ ፡ ተአምራትን ፡ ያደረገ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤

፭ ፡ ሰማያትን ፡ በብልሃት ፡ የሠራ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤

፮ ፡ ምድርን ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡ ያጸና ፤

ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፯ ብቻውን ፡ ታላላቅ ፡ ብርሃናትን ፡ የሠራ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፰ ለፀሐይ ፡ ቀንን ፡ ያስገዛው ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፱ ለጨረቃና ፡ ለከዋክብትም ፡ ሌሊትን ፡ ያስገዛቸው ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፲ ከበኵራቸው ፡ ጋር ፡ ግብጽን ፡ የመታ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፲፩ እስራኤልንም ፡ ከመካከላቸው ፡ ያወጣ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፲፪ በጸናች ፡ እጅ ፡ በተዘረጋችም ፡ ክንድ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፲፫ የኤርትራን ፡ ባሕር ፡ በየክፍሉ ፡ የከፈለ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፲፬ እስራኤልን ፡ በመካከሉ ፡ ያሳለፈ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፲፭ ፈርዖንንና ፡ ሠራዊቱን ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ የጣለ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፲፮ ሕዝቡን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የመራ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፲፯ ታላላቅ ፡ ነገሥታትን ፡ የመታ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፲፰ ብርቱዎችንም ፡ ነገሥታት ፡ የገደለ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፲፱ የአሞራውያንን ፡ ንጉሥ ፡ ሴዎንን ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፳ የባሳንን ፡ ንጉሥ ፡ ዐግን ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፳፩ ምድራቸውን ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ የሰጠ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፳፪ ለባሪያው ፡ ለእስራኤል ፡ ርስት ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፳፫ እኛን ፡ በመዋረዳችን ፡ አስበናልና ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፳፬ ከጠላቶቻችንም ፡ እጅ ፡ አድኖናልና ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፤
፳፭ ለሥጋ ፡ ሁሉ ፡ ምግብን ፡ የሚሰጥ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
፳፮ የሰማይን ፡ አምላክ ፡ አመስግኑ ፤
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።

## መዝሙር ፡ ፻፴፮ ። (፻፴፯)

፩ በባቢሎን ፡ ወንዞች ፡ አጠገብ ፡ በዚያ ፡ ተቀመጥን ፤
ጽዮንንም ፡ ባሰብናት ፡ ጊዜ ፡ አለቀስን ።
፪ በአኻያ ፡ ዛፎችዋ ፡ ላይ ፡ መሰንቆቻችንን ፡ ሰቀልን ።
፫ የማረኩን ፡ በዚያ ፡ የዝማሬን ፡ ቃል ፡ ፈለጉብን ፥
የወሰዱንም ፡— የጽዮንን ፡ ዝማሬ ፡ ዘምሩልን ፡ አሉን ።
፬ የእግዚአብሔርን ፡ ዝማሬ ፡ በባዕድ ፡ ምድር ፡
እንዴት ፡ እንዘምራለን ?
፭ ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ፥ ብረሳሽ ፥ ቀኜ ፡ ትርሳኝ ።
፮ ባላስብሽ ፥ ምላሴ ፡ በጕሮሮዬ ፡ ይጣበቅ ፤
ከደስታዬ ፡ ሁሉ ፡ በላይ ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ባልወድድ ።
፯ አቤቱ ፥ በኢየሩሳሌም ፡ ቀን ፡ የኤዶምን ፡ ልጆች ፡ አስብ ፡—
እስከ ፡ መሠረትዋ ፡ ድረስ ፡ አፍርሱ ፡ አፍርሱ ፡ ያሉአትን ።
፰ አንቺ ፡ ወራዳ ፡ የባቢሎን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥
ስለ ፡ ተበቀልሽን ፡ የሚበቀልሽ ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ።
፱ ሕፃናቶችሽን ፡ ይዞ ፡ በዓለት ፡ ላይ ፡ የሚፈጠፍጣቸው ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ።

## መዝሙር ፡ ፻፴፯ ። (፻፴፰)

የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ፥ በፍጹም ፡ ልቤ ፡ አመሰግንሃለሁ ፥
የአፌን ፡ ነገር ፡ ሰምተኸኛልና ፤
በመላእክት ፡ ፊት ፡ እዘምርልሃለሁ ።
፪ ወደ ፡ ቅዱስ ፡ መቅደስህ ፡ እሰግዳለሁ ፤
ስለ ፡ ምሕረትህና ፡ ስለ ፡ እውነትህ ፡ ስምህንም ፡ አመሰግናለሁ ፥
በሁሉ ፡ ላይ ፡ ቅዱስ ፡ ስምህን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርገሃልና ።
፫ በጠራሁህ ፡ ቀን ፡ በፍጥነት ፡ አድምጠኝ ፤
ነፍሴን ፡ በኃይልህ ፡ በብዙ ፡ አጸናሃት ።
፬ አቤቱ ፥ የምድር ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ ያመሰግኑሃል ፤
የአፍህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ሰምተዋልና ።
፭ በእግዚአብሔርም ፡ መንገድ ፡ ይዘምራሉ ፤
የእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ ታላቅ ፡ ነውና ።
፮ እግዚአብሔር ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ነውና ፥
ወደ ፡ ችግረኞችም ፡ ይመለከታልና ፤
ትዕቢተኞችንም ፡ ከሩቅ ፡ ያውቃል ።
፯ በመከራ ፡ መካከል ፡ እንኳ ፡ ብሄድ ፥ አንተ ፡ ሕያው ፡ ታደርገኛለህ ፤
በጠላቶቼ ፡ ቍጣ ፡ ላይ ፡ እጆቼን ፡ ትዘረጋለህ ፥
ቀኝህም ፡ ታድነኛለች ።
፰ እግዚአብሔር ፡ ብድራትን ፡ ይመልስልኛል ፤
አቤቱ ፥ ምሕረትህ ፡ ለዘላለም ፡ ነው ፤
አቤቱ ፥ የእጅህን ፡ ሥራ ፡ ቸል ፡ አትበል ።

## መዝሙር ፡ ፻፴፰ ። (፻፴፱)

ለመዘምራን ፡ አለቃ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩ አቤቱ ፥ መረመርኸኝ ፥ አወቅኸኝም ።
፪ አንተ ፡ መቀመጤንና ፡ መነሣቴን ፡ አወቅህ ፤
አሳቤን ፡ ሁሉ ፡ ከሩቅ ፡ አስተዋልህ ።
፫ ፍለጋዬንና ፡ ዕረፍቴን ፡ አንተ ፡ መረመርህ ፤
መንገዶቼን ፡ ሁሉ ፡ ቀድመህ ፡ አወቅህ ፥
፬ የዓመፃ ፡ ቃል ፡ በአንደበቴ ፡ እንደሌለ ።
፭ አቤቱ ፥ አንተ ፡ እነሆ ፡ የቀድሞውንና ፡ የኋላውን ፡ አወቅህ ፤

አንተ፡ፈጠርኸኝ÷እጅህንም፡በላዬ፡አደረግህ።
፮፤ እውቀትህ፡ከእኔ፡ይልቅ፡ተደነቀች፤
በረታች÷ወደ፡እርስዋም፡ለመድረስ፡አል
ችልም።
፯፤ ከመንፈስህ፡ወዴት፡እሄዳለሁ?
ከፊትህስ፡ወዴት፡እሸሻለሁ?
፰፤ ወደ፡ሰማይ፡ብወጣ÷አንተ፡በዚያ፡ነህ፤
ወደ፡ሲኦልም፡ብወርድ÷በዚያ፡አለህ።
፱፤ እንደ፡ንስር፡የንጋትን፡ክንፍ፡ብወስድ÷
እስከ፡ባሕር፡መጨረሻም፡ብበርር÷
፲፤ በዚያ፡እጅህ፡ትመራኛለች÷
ቀኝህም፡ትይዘኛለች።
፲፩፤ በውኑ፡ጨለማ፡ትሸፍነኛለች፡ብል÷
ሌሊት፡በዙሪያዬ፡ብርሃን፡ትሆናለች፤
፲፪፤ ጨለማ፡በአንተ፡ዘንድ፡አይጨልምምና÷
ሌሊትም፡እንደ፡ቀን፡ታበራለችና፤
እንደ፡ጨለማዋ፡እንዲሁ፡ብርሃንዋ፡ነው።
፲፫፤ አቤቱ÷አንተ፡ኵላሊቴን፡ፈጥረሃልና÷
በእናቴም፡ሆድ፡ሰውረኸኛል።
፲፬፤ ግሩምና፡ድንቅ፡ሆኜ፡ተፈጥሬአለሁና፡አመ
ሰግንሃለሁ፤
ሥራህ፡ድንቅ፡ነው÷ነፍሴም፡እጅግ፡ታው
ቀዋለች።
፲፭፤ እኔ፡በስውር፡በተሠራሁ፡ጊዜ÷
አካሌም፡በምድር፡ታች፡በተሠራ፡ጊዜ÷
አጥንቶቼ፡ከአንተ፡አልተሰወሩም።
፲፮፤ ያልተሠራ፡አካሌን፡ዓይኖችህ፡አዩኝ፤
የተፈጠሩ፡ቀኖቼ፡ሁሉ፡
አንድ፡ስንኳ፡ሳይኖር፡በመጽሐፍህ፡ተጻፉ።
፲፯፤ አቤቱ÷አሳቦችህ፡በእኔ፡ዘንድ፡እንደ፡ምን፡
እጅግ፡የተከበሩ፡ናቸው!
ቍጥራቸውም፡እንደ፡ምን፡በዛ!
፲፰፤ ብቈጥራቸው፡ከአሸዋ፡ይልቅ፡ይበዛሉ፤
ተነሣሁም÷እኔም፡ገና፡ከአንተ፡ጋር፡ነኝ።
፲፱፤ አቤቱ÷አንተ፡ኃጢአተኞችን፡የምትገድል፡
ከሆንህስ÷
የደም፡ሰዎች፡ሆይ÷ከእኔ፡ፈቀቅ፡በሉ።
፳፤ በክፋት፡ይናገሩብሃልና፤
ጠላቶችህም፡በከንቱ፡ያምፁብሃል።
፳፩፤ አቤቱ÷የሚጠሉህን፡እኔ፡የጠላሁ፡አይደለ
ሁምን?
ስለ፡ጠላቶችህም፡አልተሰቀቀሁምን?
፳፪፤ ፍጹም፡ጥል፡ጠላኋቸው÷ጠላቶችም፡ሆኑኝ።
፳፫፤ አቤቱ÷መርምረኝ፡ልቤንም፡እወቅ፤
ፍተነኝ፡መንገዴንም፡እወቅ፤
፳፬፤ በደልንም፡በእኔ፡ውስጥ፡ብታገኝ፡እይ፤
የዘላለምንም፡መንገድ፡ምራኝ።

## መዝሙር፡፻፴፱።(፻፵)

ለመዘምራን፡አለቃ፡የዳዊት፡መዝሙር።

፩፤ ፪፤ አቤቱ÷ከክፉ፡ሰው፡አድነኝ÷
በልባቸውም፡ክፉ፡ከሰቡ፡
ከዓመፀኞች፡ሰዎች፡ጠብቀኝ፤
ቀኑን፡ሁሉ፡ለሰልፍ፡ይከማቻሉ።
ምላሳቸውን፡እንደ፡እባብ፡ሳሉ፤ ፫፤
ከከንፈራቸው፡በታች፡የእፉኝት፡መርዝ፡
ነው።
፬፤ አቤቱ÷ከኃጢአተኞች፡እጅ፡ጠብቀኝ÷
እርምጃዬንም፡ሊያሰናክሉ፡ከመከሩ፡
ከዓመፀኞች፡አድነኝ።
፭፤ ትዕቢተኞች፡ወጥመድን፡ሰወሩብኝ÷
ለእግሮቼም፡የወጥመድ፡ገመድን፡ዘረጉ፤
በመንገድ፡ዕንቅፋትን፡አኖሩ።
፮፤ እግዚአብሔርንም፦አንተ፡አምላኬ፡ነህ፤
የልመናዬን፡ቃል÷አቤቱ÷አድምጥ፡አል
ሁት።
፯፤ አቤቱ÷ጌታዬ÷የመድኃኒቴ፡ጕልበት÷
በሰልፍ፡ቀን፡ራሴን፡ሸፈንህ።
፰፤ አቤቱ÷ከምኞቴ፡የተነሣ፡ለኃጢአተኞች፡አት
ስጠኝ፤
በላዬ፡ተማከሩ፤እንዳይኰሩ፡አትተወኝ።
፱፤ የሚከብቡኝን፡ራስ፡የከንፈራቸው፡ክፋት፡
ይክደናቸው።
፲፤ የእሳት፡ፍም፡በላያቸው፡ይውደቅ፤
እንዳይነሡም፡ወደ፡እሳትና፡ወደ፡ማዕበል፡
ይጣሉ።
፲፩፤ ተናጋሪ፡ሰው፡በምድር፡ውስጥ፡አይጸናም፤
ዓመፀኛን፡ሰው፡ክፋት፡ለጥፋት፡ይፈልገዋል።
፲፪፤ እግዚአብሔር፡ለድሀ፡ዳኝነትን፡
ለችግረኛም፡ፍርድን፡እንዲያደርግ፡አወቅሁ።
፲፫፤ ጻድቃንም፡በእውነት፡ስምህን፡ያመሰግናሉ፤
ቀኖችም፡በፊትህ፡ይኖራሉ።

## መዝሙር፡፻፵።(፻፵፩)

የዳዊት፡መዝሙር።

፩፤ አቤቱ÷ወደ፡አንተ፡ጮኽሁ፤ስማኝ፤
ወደ፡አንተ፡ስጮኽም፡የልመናዬን፡ቃል፡
አድምጥ።
፪፤ ጸሎቴን፡በፊትህ፡እንደ፡ዕጣን፡ተቀበልልኝ÷
እጅ፡መንሣቴም፡እንደ፡ሠርክ፡መሥዋዕት፡
ትሁን።
፫፤ አቤቱ÷ለአፌ፡ጠባቂ፡አኑር÷
የከንፈሮቼንም፡መዝጊያ፡ጠብቅ።
፬፤ ልቤን፡ወደ፡ክፉ፡ነገር፡አትመልሰው÷
ዓመፅን፡ከሚያደርጉ፡ሰዎች፡ጋር፡
ለኃጢአት፡ምክንያት፡እንዳልሰጥ፤
ከምርጦቻቸውም፡ጋር፡አልተባበር።
፭፤ ጻድቅ፡በምሕረት፡ይገሥጸኝ÷ይዝለፈኝም÷
የኃጢአተኛ፡ዘይት፡ግን፡ራሴን፡አይቀባ፤
ጸሎቴ፡ገና፡በክፋታቸው፡ላይ፡ነውና።
፮፤ ኃያላኖቻቸው፡በዓለት፡አጠገብ፡ተጣሉ፤
ጣፋጭ፡ናትና፡ቃሌን፡ይሰማሉ።
፯፤ በምድር፡ላይ፡እንደ፡ተሰነጠቀ፡እንደ፡መሬት፡
ጓል÷
እንዲሁ፡አጥንቶቻችን፡በሲኦል፡ተበተኑ።
፰፤ አቤቱ፡ጌታ÷ዓይኖቼ፡ወደ፡አንተ፡ናቸውና፤
በአንተ፡ታመንሁ÷ነፍሴን፡አታውጣት።
፱፤ ከሰወሩብኝ፡ወጥመድ÷

ዓመፅንም ፡ ከሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ ዕንቅፋት ፡
ጠብቀኝ ።
፲፤ እኔ ፡ ብቻዬን ፡ እስካልፍ ፡ ድረስ ፡
ኃጢአተኞች ፡ በወጥመዳቸው ፡ ይውደቁ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፩ ። (፻፵፪)

ጸሎት ፤

በዋሻ ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፤ የዳዊት ፡ ትምህርት ።

፩፤ በቃሌ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኽሁ ፤
በቃሌ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለመንሁ ።
፪፤ ልመናዬን ፡ በፊቱ ፡ አፈስሳለሁ ፤
መከራዬንም ፡ በፊቱ ፡ እናገራለሁ ።
፫፤ ነፍሴ ፡ በውስጤ ፡ ባለቀች ፡ ጊዜ ፡ መንገዴን ፡
አወቅህ ፤
በምሄድበት ፡ በዚያች ፡ መንገድ ፡ ወጥመድን ፡
ሰወሩብኝ ።
፬፤ ወደ ፡ ቀኝ ፡ ተመለከትሁ ፡ አየሁም ÷
የሚያውቀኝም ፡ አጣሁ ፤
መሸሸጊያም ፡ የለኝም ÷ ስለ ፡ ነፍሴም ፡ የሚመ
ራመር ፡ የለም ።
፭፤ አቤቱ ÷ ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኽሁ ፡—
አንተ ፡ ተስፋዬ ፡ ነህ ÷
በሕያዋንም ፡ ምድር ፡ አንተ ፡ እድል ፡ ፈንታዬ ፡
ነህ ፡ አልሁ ።
፮፤ እጅግ ፡ ተቸግሬአለሁና ፡ ወደ ፡ ልመናዬ ፡ አድ
ምጥ ፤
በርትተውብኛልና ፡ ከሚያሳድዱኝ ፡ አድነኝ ።
፯፤ አቤቱ ÷ ስምህን ፡ አመሰግን ፡ ዘንድ ፡
ነፍሴን ፡ ከወህኒ ፡ አውጣት ፤
ዋጋዬን ፡ እስክትሰጠኝ ፡ ድረስ ፡
ጻድቃን ፡ እኔን ፡ ይጠብቃሉ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፪ ። ( ፻፵፫ )

ልጁ ፡ ባሳደደው ፡ ጊዜ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ አቤቱ ÷ ጸሎቴን ፡ ስማ ፤
በእውነትህ ፡ ልመናዬን ፡ አድምጥ ÷
በጽድቅህም ፡ መልስልኝ ።
፪፤ ሕያው ፡ ሁሉ ፡ በፊትህ ፡ ጻድቅ ፡ አይደለምና ፡
ከባሪያህ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ፍርድ ፡ አትግባ ።
፫፤ ጠላት ፡ ነፍሴን ፡ አሳድዶአታል ÷
ሕይወቴንም ፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡ አጐስቍሎ
አታል ፤
ቀድሞ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ሰው ፡ በጨለማ ፡ አኑሮ
ኛል ።
፬፤ ነፍሴ ፡ በውስጤ ፡ አለቀችብኝ ÷
ልቤም ፡ በውስጤ ፡ ደነገጠብኝ ።
፭፤ የቀድሞውን ፡ ዘመን ፡ አሰብሁ ÷
ሥራህንም ፡ ሁሉ ፡ አሰላሰልሁ ፤
የእጅህንም ፡ ሥራ ፡ ተመለከትሁ ።
፮፤ እጆቼን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ዘረጋሁ ፤
ነፍሴም ፡ እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ አንተን ፡ ተጠ
ማች ።
፯፤ አቤቱ ÷ ፈጥነህ ፡ ስማኝ ፤ ነፍሴ ፡ አልቃለች ፤
ፊትህን ፡ ከኔ ፡ አትመልስ ÷
ወደ ፡ ጕድጓድም ፡ እንደሚወርዱ ፡ አልሁን ።
፰፤ አንተን ፡ ታምኜለሁና ፡
በማለዳ ፡ ምሕረትህን ፡ አሰማኝ ፤
አቤቱ ÷ ነፍሴን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ አንሥቻለሁና ፡
የምሄድበትን ፡ መንገድ ፡ አስታውቀኝ ።
፱፤ አቤቱ ÷ ወደ ፡ አንተ ፡ ተማፅኜለሁና ፡
ከጠላቶቼ ፡ አድነኝ ።
፲፤ አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነህና ፡ ፈቃድህን ፡ ለማድረግ ፡
አስተምረኝ ፤
ቅዱስ ፡ መንፈስህም ፡ በጽድቅ ፡ ምድር ፡ ይም
ራኝ ።
፲፩፤ አቤቱ ÷ ስለ ፡ ስምህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ፤
በጽድቅህም ፡ ነፍሴን ፡ ከመከራዋ ፡ አውጣት ።
፲፪፤ በምሕረትህ ፡ ጠላቶቼን ፡ ደምስሳቸው ÷
እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ነኝና ፡
ነፍሴን ፡ የሚያስጨንቁአትን ፡ ሁሉ ፡ አጥፋ
ቸው ።

መዝሙር ፡ ፻፵፫ ። (፻፵፬)

ስለ ፡ ጎልያድ ፤ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ አምላኬ ፡ ይባረክ ÷
ለእጆቼ ፡ ሰልፍን ÷ ለጣቶቼም ፡ ዘመቻን ፡ የሚ
ያስተምር ፤
፪፤ መሐሪዬና ፡ መሸሸጊያዬ ÷ መጠጊያዬና ፡ መድ
ኃኒቴ ፤
ረዳቴና ፡ መታመኛዬም ፤
ሕዝቤንም ፡ ከእኔ ፡ በታች ፡ የሚያስገዛልኝ ።
፫፤ አቤቱ ÷ እርሱን ፡ ታውቀው ፡ ዘንድ ፡ ሰው ፡
ምንድር ፡ ነው ?
ታስብለት ፡ ዘንድ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
፬፤ ሰው ፡ ከንቱን ፡ ነገር ፡ ይመስላል ፤
ዘመኑ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ያልፋል ።
፭፤ አቤቱ ÷ ሰማዮችህን ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አድርጋቸው ፡
ውረድም ፤
ተራሮችን ፡ ዳስሳቸው ፡ ይጢሱም ።
፮፤ መብረቆችህን ፡ ብልጭ ፡ አድርጋቸው ፡ በትና
ቸውም ፤
ፍላጾችህን ፡ ላካቸው ፡ አስደንግጣቸውም ።
፯፤፰፤ እጅህን ፡ ከአርያም ፡ ላክ ፡ አድነኝም ፡
ከብዙ ፡ ውኆች ÷ አፋቸውም ፡ ምናምንን ፡ ከሚ
ናገር ÷
ቀኛቸው ፡ የሐሰት ፡ ቀኝ ፡ ከሆነ ÷
ከባዕድ ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ አስጥለኝ ።
፱፤ አቤቱ ÷ አዲስ ፡ ቅኔ ፡ እቀኝልሃለሁ ፤
አሥር ፡ አውታር ፡ ባለው ፡ በገና ፡ እዘምርልሃ
ለሁ ።
፲፤ ለነገሥታት ፡ መድኃኒትን ፡ የሚሰጥ ÷
ባሪያውን ፡ ዳዊትን ፡ ከክፉ ፡ ሰይፍ ፡ የሚያድ
ነው ፡ እርሱ ፡ ነው ።
፲፩፤ አድነኝ ÷ አፋቸውም ፡ ምናምንን ፡ ከሚናገር ÷
ቀኛቸውም ፡ የሐሰት ፡ ቀኝ ፡ ከሆነ ÷
ከባዕድ ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ አስጥለኝ ።
፲፪፤ ልጆቻቸው ፡ በጕልማስነታቸው ፡ እንደ ፡ አዲስ ፡
አትክልት ፡ የሆኑ ÷

ሴቶች ፡ ልጆቻቸውም ፡ እንደ ፡ እልፍኝ ፡ ያማሩና ፡ ያጌጡ ፤
፲፫ ዕቃ ፡ ቤቶቻቸውም ፡ የተሞሉ ፡ በየዓይነቱ ፡ ዕቃ ፡ የሚሰጡ ፥
በጎቻቸውም ፡ ብዙ ፡ የሚወልዱ ፥
በማሰማርያቸውም ፡ የሚበዙ ፥
፲፬ ላሞቻቸውም ፡ የሚሰቡ ፤
ቅጥራቸውም ፡ መፍረሻና ፡ መውጫ ፡ የሌለው ፥
በአደባባዮቻቸውም ፡ ዋይታ ፡ የሌለ ፤
፲፭ እንደዚህ ፡ የሚሆን ፡ ሕዝብ ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ፤
እግዚአብሔር ፡ አምላኩ ፡ የሆነ ፡ ሕዝብ ፡ ምስጉን ፡ ነው ።

## መዝሙር ፡ ፻፵፬ ። (፻፵፭)

የዳዊት ፡ የምስጋና ፡ መዝሙር ።

፩ አምላኬ ፡ ንጉሤ ፡ ሆይ ፥ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርግሃለሁ ፥
ስምህንም ፡ ለዘላለም ፡ ዓለምም ፡ እባርካለሁ ።
፪ በየቀኑ ፡ ሁሉ ፡ እባርክሃለሁ ፥
ስምህንም ፡ ለዘላለም ፡ ዓለምም ፡ አመሰግናለሁ ።
፫ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡ እጅግም ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ፤
ለታላቅነቱም ፡ ፍጻሜ ፡ የለውም ።
፬ ትውልደ ፡ ትውልድ ፡ ሥራህን ፡ ያመሰግናሉ ፥
ኃይልህንም ፡ ያወራሉ ።
፭ የቅድስናህን ፡ ግርማ ፡ ክብር ፡ ይናገራሉ ፥
ተአምራትህንም ፡ ይነጋገራሉ ።
፮ የግርማህንም ፡ ኃይል ፡ ይናገራሉ ፥
ታላቅነትህንም ፡ ይነጋገራሉ ፥
ብርታትህንም ፡ ይነጋገራሉ ።
፯ የቸርነትህን ፡ ብዛት ፡ መታሰብ ፡ ያወጣሉ ፥
በጽድቅህም ፡ ሐሤትን ፡ ያደርጋሉ ።
፰ እግዚአብሔር ፡ ርኅሩኅና ፡ መሐሪ ፡ ነው ፥
ከቍጣ ፡ የራቀ ፥ ምሕረቱም ፡ ብዙ ፡ ነው ፤
፱ እግዚአብሔር ፡ ለሚታገሡት ፡ ቸር ፡ ነው ።
ምሕረቱም ፡ በሥራው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነው ።
፲ አቤቱ ፥ ሥራህ ፡ ሁሉ ፡ ያመሰግኑሃል ፥
ቅዱሳንህም ፡ ይባርኩሃል ።
፲፩ የመንግሥትህን ፡ ክብር ፡ ይናገራሉ ፥
ኃይልህንም ፡ ይነጋገራሉ ፥
፲፪ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ኃይልህን ፡
የመንግሥትህንም ፡ ግርማ ፡ ክብር ፡ ያስታውቁ ፡ ዘንድ ።
፲፫ መንግሥትህ ፡ የዘላለም ፡ መንግሥት ፡ ናት ፥
ግዛትህም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
፲፬ እግዚአብሔር ፡ በቃሉ ፡ የታመነ ፡ ነው ፥
በሥራውም ፡ ሁሉ ፡ ጻድቅ ፡ ነው ፤
እግዚአብሔር ፡ የተፍገመገሙትን ፡ ሁሉ ፡ ይደግፋቸዋል ፥
የወደቁትንም ፡ ያነሣቸዋል ።
፲፭ የሁሉ ፡ ዓይን ፡ አንተን ፡ ተስፋ ፡ ያደርጋል ፤
አንተም ፡ ምግባቸውን ፡ በየጊዜው ፡ ትሰጣቸዋለህ ።
፲፮ አንተ ፡ እጅህን ፡ ትከፍታለህ ፥
ሕይወት ፡ ላለውም ፡ ሁሉ ፡ መልካምን ፡ ታጠግበለህ ።
፲፯ እግዚአብሔር ፡ በመንገዱ ፡ ሁሉ ፡ ጻድቅ ፡ ነው ፡
በሥራውም ፡ ሁሉ ፡ ቸር ፡ ነው ።
፲፰ እግዚአብሔር ፡ ለሚጠሩት ፡ ሁሉ ፥
በእውነት ፡ ለሚጠሩት ፡ ሁሉ ፡ ቅርብ ፡ ነው ።
፲፱ ለሚፈሩት ፡ ምኞታቸውን ፡ ያደርጋል ፥
ልመናቸውንም ፡ ይሰማል ፡ ያድናቸዋልም ።
፳ እግዚአብሔር ፡ የሚወድዱትን ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቃል ፤
ኃጢአተኞችንም ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋል ።
፳፩ አፌ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ምስጋና ፡ ይናገራል ፤
ሥጋም ፡ ሁሉ ፡ ለዘላለም ፡ ዓለም ፡ የተቀደሰውን ፡ ስሙን ፡ ይባርክ ።

## መዝሙር ፡ ፻፵፭ ። (፻፵፮)

የሐጌና ፡ የዘካርያስ ፡ መዝሙር ።

፩ ሃሌ ፡ ሉያ ።
ነፍሴ ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኚ ።
፪ በሕይወቴ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግናለሁ ፤
በምኖርበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ለአምላኬ ፡ እዘምራለሁ ።
፫ ማዳን ፡ በማይችሉ ፡ በሰው ፡ ልጅችና ፡ በአለቆች ፡ አትታመኑ ።
፬ ነፍሱ ፡ ትወጣለች ፡ ወደ ፡ መሬቱም ፡ ይመለሳል ፤
ያን ፡ ጊዜ ፡ ምክሩ ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋል ።
፭ የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ረዳቱ ፡ የሆነ ፡
ተስፋውም ፡ በአምላኩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ፤
፮ እርሱም ፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ ባሕርንም ፥ በእነርሱ ፡ ያለውንም ፡ ሁሉ ፡ የፈጠረ ፤
እውነትን ፡ ለዘላለም ፡ የሚጠብቅ ፤
፯ ለተበደሉት ፡ የሚፈርድ ፥
ለተራቡ ፡ ምግብን ፡ የሚሰጥ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ የታሰሩትን ፡ ይፈታል ፤
፰ እግዚአብሔር ፡ የወደቁትን ፡ ያነሣል ፤
እግዚአብሔር ፡ ዕውሮችን ፡ ጥበበኞች ፡ ያደርጋቸዋል ፤
እግዚአብሔር ፡ ጻድቃንን ፡ ይወድዳል ፤
፱ እግዚአብሔር ፡ ስደተኞችን ፡ ይጠብቃል ፤
ድሀ ፡ አደጎችንና ፡ በልቴቶችን ፡ ይቀበላል ፤
የኃጢአተኞችንም ፡ መንገድ ፡ ያጠፋል ።
፲ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ይነግሣል ፤
ጽዮን ፡ ሆይ ፥ አምላክሽ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

## መዝሙር ፡ ፻፵፮ ። (፻፵፯)

የሐጌና ፡ የዘካርያስ ፡ መዝሙር ።

፩ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፥ መዝሙር ፡ መልካም ፡ ነውና ።
ለአምላካችን ፡ ምስጋና ፡ ያማረ ፡ ነው ።
፪ እግዚአብሔር ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ይሠራል ፥
ከእስራኤልም ፡ የተበተኑትን ፡ ይሰበስባል ።
፫ ልባቸውን ፡ የቈሰሉትን ፡ ይፈውሳል ፥

ሕማማቸውንም ፡ ይጠግናል ።
፬፤ የከዋክብትንም ፡ ብዛት ፡ ይቈጥራል ፥
ሁሉንም ፡ በየስማቸው ፡ ይጠራቸዋል ።
፭፤ ጌታችን ፡ ታላቅ ፡ ነው ፥ ኃይሉም ፡ ታላቅ ፡ ነው ፥
ለጥበቡም ፡ ቍጥር ፡ የለውም ።
፮፤ እግዚአብሔር ፡ የዋሃንን ፡ ያነሣል ፥
ኃጢአተኞችን ፡ ግን ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ድረስ ፡ ያዋርዳል ።
፯፤ ለእግዚአብሔር ፡ በምስጋና ፡ ዘምሩ ፥
ለአምላካችንም ፡ በመሰንቆ ፡ ዘምሩ ፤
፰፤ ሰማዩን ፡ በደመናት ፡ ይሸፍናል ፥
ለምድርም ፡ ዝናብን ፡ ያዘጋጃል ፤
ሣርን ፡ በተራሮች ፡ ላይ ፡ ያበቅላል ፤
ለምለሙንም ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ጥቅም ።
፱፤ ለሚጠሩት ፡ ለቍራዎች ፡ ጫጩቶች ፡
ለእንስሶችም ፡ ምግባቸውን ፡ ይሰጣል ።
፲፤ የፈረስን ፡ ኃይል ፡ አይወድድም ፥
በሰውም ፡ ጭን ፡ አይደሰትም ።
፲፩፤ እግዚአብሔር ፡ በሚፈሩት ፥
በምሕረቱም ፡ በሚታመኑ ፡ ይደሰታል ።

~~መዝሙር ፡ ፻፵፯ ።~~

(፲፪) ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኚ ፥
(፲፫) ጽዮንም ፡ ሆይ ፥ ለአምላክሽ ፡ እልል ፡ በዪ ፤
የደጆችሽን ፡ መወርወሪያ ፡ አጽንቶአልና ፥
ልጆችንም ፡ በውስጥሽ ፡ ባርኮአልና ።
(፲፬) በወሰንሽም ፡ ሰላምን ፡ አደረገ ፥
የስንዴንም ፡ ስብ ፡ አጠገበሽ ።
(፲፭) ነገሩን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ይሰድዳል ፥
ቃሉም ፡ እጅግ ፡ ፈጥኖ ፡ ይሮጣል ።
(፲፮) አመዳዩን ፡ እንደ ፡ ባዘቶ ፡ ይሰጣል ፤
ጉሙን ፡ እንደ ፡ አመድ ፡ ይበትነዋል ፤
(፲፯) በረዶውን ፡ እንደ ፡ ፍርፋሪ ፡ ያወርዳል ፤
በበረዶውስ ፡ ፊት ፡ ማን ፡ ይቆማል ?
(፲፰) ቃሉን ፡ ልኮ ፡ ያቀልጠዋል ፤
ነፋሱን ፡ ያነፍሳል ፥ ውኆችንም ፡ ያፈስሳል ።
(፲፱) ቃሉን ፡ ለያዕቆብ ፥
ሥርዓቱንና ፡ ፍርዱን ፡ ለእስራኤል ፡ ይናገራል ።
(፳) ለሌሎች ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ አላደረገም ፥
ፍርዱንም ፡ አልገለጠላቸውም ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

## መዝሙር ፡ ፻፵፰ ።

የሐጌና ፡ የዘካርያስ ፡ መዝሙር ፡

፩፤ ሃሌ ፡ ሉያ ።
እግዚአብሔርን ፡ ከሰማያት ፡ አመስግኑት ፤
በአርያም ፡ አመስግኑት ።
፪፤ መላእክቱ ፡ ሁሉ ፥ አመስግኑት ፤
ሠራዊቱ ፡ ሁሉ ፥ አመስግኑት ።
፫፤ ፀሐይና ፡ ጨረቃ ፥ አመስግኑት ፤
ከዋክብትና ፡ ብርሃን ፡ ሁሉ ፥ አመስግኑት ።
፬፤ ሰማየ ፡ ሰማያት ፥ አመስግኑት ፤
የሰማያት ፡ በላይም ፡ ውኃ ።
፭፤ እርሱ ፡ ብሎአልና ፥ ሆኑም ፤
እርሱም ፡ አዝዞአልና ፥ ተፈጠሩም ፤
የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ያመስግኑት ።
፮፤ ለዘላለም ፡ ዓለም ፡ አቆማቸው ፤
ትእዛዝን ፡ ሰጠ ፥ አያልፉምም ።
፯፤ እባቦች ፡ ጥልቆችም ፡ ሁሉ ፥
እግዚአብሔርን ፡ ከምድር ፡ አመስግኑት ፤
፰፤ እሳትና ፡ በረዶ ፡ አመዳይና ፡ ውርጭ ፥
ቃሉን ፡ የሚያደርግ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስም ፤
፱፤ ተራሮች ፡ ኰረብቶችም ፡ ሁሉ ፥
የሚያፈራም ፡ ዛፍ ፡ ዝግባም ፡ ሁሉ ፤
፲፤ አራዊትም ፡ እንስሳትም ፡ ሁሉ ፥
ተንቀሳቃሾችም ፡ የሚበርሩ ፡ ወፎችም ፤
፲፩፤ የምድር ፡ ነገሥታት ፡ አሕዛብም ፡ ሁሉ ፥
አለቆች ፡ የምድርም ፡ ፈራጆች ፡ ሁሉ ፤
፲፪፤ ጕልማሶችና ፡ ቈነጃጅቶች ፥
ሽማግሌዎችና ፡ ልጆች ፤
፲፫፤ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ያመስግኑ ፤
ስሙ ፡ ብቻውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎአልና ፥
ምስጋናውም ፡ በሰማይና ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ነው ።
፲፬፤ የሕዝቡንም ፡ ቀንድ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ፤
የቅዱሳኑንም ፡ ሁሉ ፡ ምስጋና ፡
ወደ ፡ እርሱ ፡ ለቀረበ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሕዝብ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

## መዝሙር ፡ ፻፵፱ ።

፩፤ ሃሌ ፡ ሉያ ።
ለእግዚአብሔር ፡ አዲሱን ፡ ቅኔ ፡ ተቀኙለት ፤
ምስጋናው ፡ በቅዱሳኑ ፡ ጉባኤ ፡ ነው ።
፪፤ እስራኤል ፡ በፈጣሪው ፡ ደስ ፡ ይበለው ፥
የጽዮንም ፡ ልጆች ፡ በንጉሣቸው ፡ ሐሤትን ፡ ያድርጉ ።
፫፤ ስሙን ፡ በዘፈን ፡ ያመስግኑ ፥
በከበሮና ፡ በመሰንቆም ፡ ይዘምሩለት ።
፬፤ እግዚአብሔር ፡ በሕዝቡ ፡ ተደስቶአልና ፥
የዋሃንንም ፡ በማዳኑ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋልና ።
፭፤ ቅዱሳን ፡ በክብር ፡ ይመኩ ፤
በምንጣፋቸውም ፡ ላይ ፡ ሐሤትን ፡ ያድርጉ ።
፮፤ የእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ በጕሮሮአቸው ፡ ነው ፤
ሁለት ፡ አፍ ፡ ያለውም ፡ ሰይፍ ፡ በእጃቸው ፡ ነው ፥
፯፤ በአሕዛብ ፡ ላይ ፡ በቀልን ፥
በሰዎችም ፡ መካከል ፡ ቅጣትን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፤
፰፤ ንጉሦቻቸውን ፡ በሰንሰለት ፥
አለቆቻቸውንም ፡ በእግር ፡ ብረት ፡ ያስሩ ፡ ዘንድ ፤
፱፤ የተጻፈውን ፡ ፍርድ ፡ ያደርጉባቸው ፡ ዘንድ ።
ለቅዱሳን ፡ ሁሉ ፡ ይህች ፡ክብር ፡ ናት ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

## መዝሙር ፡ ፻፶ ።

፩፤ ሃሌ ፡ ሉያ ።
እግዚአብሔርን ፡ በመቅደሱ ፡ አመስግኑት ፤
በኃይሉ ፡ ጠፈር ፡ አመስግኑት ።

፪፡ በችሎቱ ፡ አመስግኑት ፤
በታላቅነቱ ፡ ብዛት ፡ አመስግኑት ።
፫፡ በመለከት ፡ ድምፅ ፡ አመስግኑት ፤
በበገናና ፡ በመሰንቆ ፡ አመስግኑት ።
፬፡ በከበሮና ፡ በዘፈን ፡ አመስግኑት ፤
በአውታርና ፡ በእምቢልታ ፡ አመስግኑት ።
፭፡ ድምፁ ፡ መልካም ፡ በሆነ ፡ ጸናጽል ፡ አመስግኑት ፤
እልልታ ፡ ባለው ፡ ጸናጽል ፡ አመስግኑት ።
፮፡ እስትንፋስ ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመስግን ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

# መጽሐፈ ፡ ምሳሌ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ የሰሎ
ሞን ፡ ምሳሌዎች ፤
፪፡ ጥበብንና ፡ ተግሣጽን ፡ ለማወቅ ፥
የእውቀትንም ፡ ቃል ፡ ለማስተዋል ፥
፫፡ የጥበብን ፡ ትምህርት ፡
ጽድቅንና ፡ ፍርድን ፡ ቅንነትንም ፡ ለመቀበል ፥
፬፡ ብልሃትን ፡ ለአላዋቂዎች ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡
ለጐበዛዝትም ፡ እውቀትንና ፡ ጥንቃቄን ፥
፭፡ ጠቢብ ፡ እነዚህን ፡ ከመስማት ፡ ጥበብን ፡ ይጨ
ምራል ፥
አስተዋይም ፡ መልካም ፡ ምክርን ፡ ገንዘቡ ፡
ያደርጋል ፥
፮፡ ምሳሌንና ፡ ትርጓሜን ፡
የጠቢባንን ፡ ቃልና ፡ የተሸሸገውን ፡ ነገር ፡ ለማ
ስተዋል ።

፯፡ የጥበብ ፡ መጀመሪያ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍ
ራት ፡ ነው ፤
ሰነፎች ፡ ግን ፡ ጥበብንና ፡ ተግሣጽን ፡ ይንቃሉ ።
፰፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ የአባትህን ፡ ምክር ፡ ስማ ፥
የእናትህንም ፡ ሕግ ፡ አትተው ፤
፱፡ ለራስህ ፡ የሞገስ ፡ ዘውድ ፡
ለአንገትህም ፡ ድሪ ፡ ይሆንልሃልና ።
፲፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ኃጢአተኞች ፡ ቢያባብሉህ ፡ እሺ ፡
አትበል ።
፲፩፡ ደምን ፡ ለማፍሰስ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ና ፡ እናድባ ፥
ለንጹሕም ፡ ያለ ፡ ምክንያት ፡ ወጥመድን ፡ እን
ሸምቀበት ፡ ቢሉ ፤
፲፪፡ በሕይወታቸው ፡ ሳሉ ፡ እንደ ፡ ሲኦል ፡ ሆነን ፡
እንዋጣቸው ፥
በሙሉም ፡ ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ እንደሚወድቁ ፡
ይሁኑ ፤
፲፫፡ መልካሙን ፡ ሀብት ፡ ሁሉ ፡ እናገኛለን ፥
ከምርኮውም ፡ ቤታችንን ፡ እንሞላለን ፤
፲፬፡ ዕጣህን ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ጣል ፤
ለሁላችንም ፡ አንድ ፡ ከረጢት ፡ ይሁን ፡ ቢሉ ፤
፲፭፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ በመንገድ ፡ አት
ሂድ ፥
ከጎዳናቸውም ፡ እግርህን ፡ ፈቀቅ ፡ አድርግ ፤
፲፮፡ እግሮቻቸው ፡ ወደ ፡ ክፉት ፡ ይሮጣሉና ፥
ደም ፡ ለማፍሰስም ፡ ይፈጥናሉና ።
፲፯፡ መርበብ ፡ በወፎች ፡ ዓይን ፡ ፊት ፡ በከንቱ ፡ ትተ
ከላለችና ።
፲፰፡ እነርሱም ፡ በደማቸው ፡ ላይ ፡ ያደባሉ ፥
በነፍሳቸውም ፡ ላይ ፡ ይሸምቃሉ ።
፲፱፡ እንዲሁ ፡ ይህ ፡ መንገድ ፡ ትርፍን ፡ ለማግኘት ፡
የሚሳሳ ፡ ሁሉ ፡ ነው ።
የባለቤቱን ፡ ነፍስ ፡ ይነጥቃል ።

፳፡ ጥበብ ፡ በጎዳና ፡ ትጮኻለች ፤
በአደባባይ ፡ ድምፅዋን ፡ ከፍ ፡ ታደርጋለች ፤
፳፩፡ በአደባባይ ፡ ትጣራለች ፤
በከተማይቱ ፡ መግቢያ ፡ በር ፡ ቃልን ፡ ትናገራ
ለች ፦
፳፪፡ እናንት ፡ አላዋቂዎች ፥ እስከ ፡ መቼ ፡ አላዋቂ
ነት ፡ ትወድዳላችሁ ?
ፌዘኞችም ፡ ፌዝን ፡ ይፈቅዳሉ ?
ሰነፎችም ፡ እውቀትን ፡ ይጠላሉ ?

፪፤ በችሎቱ ፡ አመስግኑት ፤
በታላቅነቱ ፡ ብዛት ፡ አመስግኑት ።
፫፤ በመለከት ፡ ድምፅ ፡ አመስግኑት ፤
በበገናና ፡ በመሰንቆ ፡ አመስግኑት ።
፬፤ በከበሮና ፡ በዘፈን ፡ አመስግኑት ፤
በአውታርና ፡ በእምቢልታ ፡ አመስግኑት ።
፭፤ ድምፁ ፡ መልካም ፡ በሆነ ፡ ጸናጽል ፡ አመስግኑት ፤
እልልታ ፡ ባለው ፡ ጸናጽል ፡ አመስግኑት ።
፮፤ እስትንፋስ ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመስግን ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

# መ ጽ ሐ ፈ ፡ ም ሳ ሌ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ የሰሎ ሞን ፡ ምሳሌዎች ፤
፪፤ ጥበብንና ፡ ተግሣጽን ፡ ለማወቅ ፥
የእውቀትንም ፡ ቃል ፡ ለማስተዋል ፥
፫፤ የጥበብን ፡ ትምህርት ፡
ጽድቅንና ፡ ፍርድን ፡ ቅንነትንም ፡ ለመቀበል ፥
፬፤ ብልሃትን ፡ ለአላዋቂዎች ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡
ለጐበዛዝትም ፡ እውቀትንና ፡ ጥንቃቄን ፥
፭፤ ጠቢብ ፡ እነዚህን ፡ ከመስማት ፡ ጥበብን ፡ ይጨ ምራል ፥
አስተዋይም ፡ መልካም ፡ ምክርን ፡ ገንዘቡ ፡ ያደርጋል ፥
፮፤ ምሳሌንና ፡ ትርጓሜን ፡
የጠቢባንን ፡ ቃልና ፡ የተሸሸገውን ፡ ነገር ፡ ለማ ስተዋል ።

፯፤ የጥበብ ፡ መጀመሪያ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍ ራት ፡ ነው ፤
ሰነፎች ፡ ግን ፡ ጥበብንና ፡ ተግሣጽን ፡ ይንቃሉ ።
፰፤ ልጄ ፡ ሆይ ፥ የአባትህን ፡ ምክር ፡ ስማ ፥
የእናትህንም ፡ ሕግ ፡ አትተው ፤
፱፤ ለራስህ ፡ የሞገስ ፡ ዘውድ ፡
ለአንገትህም ፡ ድሪ ፡ ይሆንልሃልና ።
፲፤ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ኃጢአተኞች ፡ ቢያባብሉህ ፡ እሺ ፡ አትበል ።
፲፩፤ ደምን ፡ ለማፍሰስ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ና ፡ እናድብ ፥
ለንጹሕም ፡ ያለ ፡ ምክንያት ፡ ወጥመድን ፡ እን ሸምቅበት ፡ ቢሉ ፤
፲፪፤ በሕይወታቸው ፡ ሳሉ ፡ እንደ ፡ ሲኦል ፡ ሆነን ፡ እንዋጣቸው ፥
በሙሉም ፡ ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ እንደሚወድቁ ፡ ይሁኑ ፤
፲፫፤ መልካሙን ፡ ሀብት ፡ ሁሉ ፡ እናገኛለን ፥
ከምርኮውም ፡ ቤታችንን ፡ እንሞላለን ፤
፲፬፤ ዕጣህን ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ጣል ፤
ለሁላችንም ፡ አንድ ፡ ከረጢት ፡ ይሁን ፡ ቢሉ ፤
፲፭፤ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ በመንገድ ፡ አት ሂድ ፥
ከጎዳናቸውም ፡ እግርህን ፡ ፈቀቅ ፡ አድርግ ፤
፲፮፤ እግሮቻቸው ፡ ወደ ፡ ክፋት ፡ ይሮጣሉና ፥
ደም ፡ ለማፍሰስም ፡ ይፈጥናሉና ።
፲፯፤ መርበብ ፡ በወፎች ፡ ዓይን ፡ ፊት ፡ በከንቱ ፡ ትተ ከላለችና ።
፲፰፤ እነርሱም ፡ በደማቸው ፡ ላይ ፡ ያደባሉ ፥
በነፍሳቸውም ፡ ላይ ፡ ይሸምቃሉ ።
፲፱፤ እንዲሁ ፡ ይህ ፡ መንገድ ፡ ትርፍን ፡ ለማግኘት ፡ የሚሳሳ ፡ ሁሉ ፡ ነው ።
የባለቤቱን ፡ ነፍስ ፡ ይነጥቃል ።

፳፤ ጥበብ ፡ በጎዳና ፡ ትጮኻለች ፤
በአደባባይ ፡ ድምፅዋን ፡ ከፍ ፡ ታደርጋለች ፤
፳፩፤ በአደባባይ ፡ ትጣራለች ፤
በከተማይቱ ፡ መግቢያ ፡ በር ፡ ቃልን ፡ ትናገራ ለች ፡—
፳፪፤ እናንት ፡ አላዋቂዎች ፥ እስከ ፡ መቼ ፡ አላዋቂ ነት ፡ ትወድዳላችሁ ?
ፌዘኞችም ፡ ፌዝን ፡ ይፈቅዳሉ ?
ሰነፎችም ፡ እውቀትን ፡ ይጠላሉ ?

፳፫፤ ወደ፡ዘለፋዬ፡ተመለሱ፤
እነሆ፥መንፈሴን፡አፈስስላችኋለሁ፤
ቃሌን፡አስተምራችኋለሁ።
፳፬፤ በጠራሁ፡ጊዜ፡እምቢ፡ስላላችሁ፥
እጄን፡በዘረጋሁ፡ጊዜ፡ማንም፡ስላላስተዋለ፥
፳፭፤ ምክሬን፡ሁሉ፡ግን፡ቸል፡ስላላችሁ፥
ዘለፋዬንም፡ስላልፈቀዳችሁ፤
፳፮፤ እኔም፡ስለዚህ፡በጥፋታችሁ፡እስቃለሁ፤
ጥፋታችሁም፡በመጣ፡ጊዜ፡አላግጥባችኋለሁ፤
፳፯፤ ድንጋጤ፡እንደ፡ጐርፍ፡በደረሰባችሁ፡ጊዜ፥
ጥፋታችሁም፡እንደ፡ዐውሎ፡ነፋስ፡በመጣ፡
ጊዜ፥
ጭንቀና፡መከራ፡በወረደባችሁ፡ጊዜ።
፳፰፤ የዚያን፡ጊዜ፡ይጠሩኛል፥እኔ፡ግን፡አልመ
ልስም፤
ተግተው፡ይሹኛል፥ነገር፡ግን፡አያገኙኝም።
፳፱፤ እውቀትን፡ጠልተዋልና፥
እግዚአብሔርንም፡መፍራት፡አልመረጡምና፤
፴፤ ምክሬን፡አልፈቀዱምና፥
ዘለፋዬንም፡ሁሉ፡ንቀዋልና፤
፴፩፤ ስለዚህ፡የመንገዳቸውን፡ፍሬ፡ይበላሉ፥
ከራሳቸው፡ምክር፡ይጠግባሉ።
፴፪፤ አላዋቂዎችን፡ከጥበብ፡መራቅ፡ይገድላቸዋ
ልና፥
ሰነፎችንም፡ቸልተኛ፡መሆን፡ያጠፋቸዋልና።
፴፫፤ የሚሰማኝ፡ግን፡በእርጋታ፡ይቀመጣል፥
ከመከራም፡ሥጋት፡ያርፋል።

ምዕራፍ፡፪።

፩፤ ልጄ፡ሆይ፥ቃሌን፡ብትቀበል፥
ትእዛዜንም፡በአንተ፡ዘንድ፡ሸሽገህ፡ብት
ይዛት፥
፪፤ ጆሮህ፡ጥበብን፡እንዲያደምጥ፡ታደርጋለህ፥
ልብህንም፡ወደ፡ማስተዋል፡ታዘነብላለህ።
፫፤ ረቂቅ፡እውቀትን፡ብትጠራት፥
ለማስተዋልም፡ድምፅህን፡ብታነሣ፥
፬፤ እርስዋንም፡እንደ፡ብር፡ብትፈላልጋት፥
እርስዋንም፡እንደ፡ተቀበረ፡ገንዘብ፡ብትሻት፤
፭፤ የዚያን፡ጊዜ፡እግዚአብሔርን፡መፍራት፡ታው
ቃለህ፥
የአምላክንም፡እውቀት፡ታገኛለህ።
፮፤ እግዚአብሔር፡ጥበብን፡ይሰጣልና፤
ከአፉም፡እውቀትና፡ማስተዋል፡ይወጣሉ፤
፯፤ እርሱ፡ለቅኖች፡ደኅንነትን፡ያከማቻል፤
ያለ፡ነውር፡ለሚሄዱትም፡ጋሻ፡ነው፤
፰፤ የፍርድን፡ጎዳና፡ይጠብቃል፤
የቅዱሳኑንም፡መንገድ፡ያጸናል።
፱፤ የዚያን፡ጊዜ፡ጽድቅንና፡ፍርድን፡
ቅንነትንና፡መልካም፡መንገድን፡ሁሉ፡ታስ
ተውላለህ።
፲፤ ጥበብ፡ወደ፡ልብህ፡ትገባለችና፥
እውቀትም፡ነፍስህን፡ደስ፡ታሰኛለችና፤
፲፩፤ ጥንቃቄ፡ይጠብቅሃል፥
ማስተዋልም፡ይጋርድሃል፥
፲፪፤ ከክፉ፡መንገድ፡አንተን፡ለማዳን፥
ጠማማ፡ነገርን፡ከሚናገሩም፡ሰዎች፤
፲፫፤ እነርሱም፡በጨለማ፡መንገድ፡ይሄዱ፡ዘንድ፡
የቀናውን፡ጎዳና፡የሚተዉ፥
፲፬፤ ክፉ፡በመሥራት፡ደስ፡የሚላቸው፡
በጠማማነትም፡ደስታን፡የሚያደርጉ፥
፲፭፤ መንገዳቸውን፡የሚጠመዝዙ፡
አካሄዳቸውንም፡የሚያጣምሙ፡ናቸው፤
፲፮፤ ከጋለሞታ፡ሴት፡አንተን፡ለመታደግ፥
ቃልዋን፡ከምታለዝብ፡ከሌላዪቱም፡ሴት፤
፲፯፤ የሕፃንነት፡ወዳጅዋን፡የምትተው፡
የአምላክዋንም፡ቃል፡ኪዳን፡የምትረሳ፤
፲፰፤ ቤትዋ፡ወደ፡ሞት፡ያዘነበለ፡ነው፥
አካሄድዋም፡ወደ፡ሙታን፡ጥላ።
፲፱፤ ወደ፡እርስዋ፡የሚገቡ፡ሁሉ፡አይመለሱም፥
የሕይወትንም፡ጎዳና፡አያገኙም፤
፳፤ አንተም፡በደጋግ፡ሰዎች፡መንገድ፡እንድት
ሄድ፡
የጻድቃንንም፡ጎዳና፡እንድትጠብቅ።
፳፩፤ ቅኖች፡በምድር፡ላይ፡ይቀመጣሉና፥
ፍጹማንም፡በእርስዋ፡ይኖራሉና፤
፳፪፤ ኀጥአን፡ግን፡ከምድር፡ይጠፋሉ፥
ዓመፀኞችም፡ከእርስዋ፡ይነጠቃሉ።

ምዕራፍ፡፫።

፩፤ ልጄ፡ሆይ፥ሕጌን፡አትርሳ፥
ልብህም፡ትእዛዛቴን፡ይጠብቅ።
፪፤ ብዙ፡ዘመናትና፡ረጅም፡ዕድሜ፡
ሰላምም፡ይጨምሩልሃልና።
፫፤ ምሕረትና፡እውነት፡ከአንተ፡አይራቁ፤
በአንገትህ፡እሰራቸው፤
በልብህ፡ጽላት፡ጻፋቸው።
፬፤ በእግዚአብሔርና፡በሰው፡ፊትም፡
ሞገስንና፡መልካም፡ዝናን፡ታገኛለህ።
፭፤ በፍጹም፡ልብህ፡በእግዚአብሔር፡ታመን፥
በራስህም፡ማስተዋል፡አትደገፍ፤
፮፤ በመንገድህ፡ሁሉ፡እርሱን፡እወቅ፥
እርሱም፡ጎዳናህን፡ያቀናልሃል።
፯፤ በራስህ፡አስተያየት፡ጠቢብ፡አትሁን፤
እግዚአብሔርን፡ፍራ፥ከክፋትም፡ራቅ፤
፰፤ ይህም፡ለሥጋህ፡ፈውስ፡ይሆንልሃል፥
ለአጥንትህም፡ጠገን።
፱፤ እግዚአብሔርን፡ከሀብትህ፡አክብር፥
ከፍሬህም፡ሁሉ፡በኵራት፤
፲፤ ጐተራህም፡እህልን፡ይሞላል፥
መጥመቂያህም፡በወይን፡ጠጅ፡ሞልታ፡ትት
ረፈረፋለች።

፲፩፤ ልጄ፡ሆይ፥የእግዚአብሔርን፡ተግሣጽ፡
አትናቅ፥
በገሥጸህም፡ጊዜ፡አትመረር።
፲፪፤ እግዚአብሔር፡የወደደውን፡ይገሥጻልና፥
አባት፡የሚወድደውን፡ልጁን፡እንደሚገሥጽ።
፲፫፤ ጥበብን፡የሚያገኝ፡ሰው፡ምስጉን፡ነው፥

ማስተዋልንም ፡ ገንዘቡ ፡ የሚያደርግ ፤

፲፬ ፡ በወርቅና ፡ በብር ፡ ከመነገድ ፡ ይልቅ ፡ በእር ስዋ ፡ መነገድ ፡ ይሻላልና ።

፲፭ ፡ ከቀይ ፡ ዕንቍም ፡ ትከብራለች ፥ የተከበረም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አይተካከላትም ።

፲፮ ፡ በቀኝዋ ፡ ረጅም ፡ ዘመን ፡ ነው ፥ በግራዋም ፡ ባለጠግነትና ፡ ክብር ።

፲፯ ፡ መንገድዋ ፡ የደስታ ፡ መንገድ ፡ ነው ፥ ጎዳናዋም ፡ ሁሉ ፡ ሰላም ፡ ነው ።

፲፰ ፡ እርስዋ ፡ ለሚይዙአት ፡ የሕይወት ፡ ዛፍ ፡ ናት ፥ የተመረኰዘባትም ፡ ሁሉ ፡ ምስጉን ፡ ነው ።

፲፱ ፡ እግዚአብሔር ፡ በጥበብ ፡ ምድርን ፡ መሠረተ ፥ በማስተዋልም ፡ ሰማያትን ፡ አጸና ።

፳ ፡ በእውቀቱ ፡ ቀላያት ፡ ተቀደዱ ፥ ደመናትም ፡ ጠልን ፡ ያንጠባጥባሉ ።

፳፩ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ እነዚህ ፡ ከዓይኖችህ ፡ አይራቁ ፤ መልካም ፡ ጥበብንና ፡ ጥንቃቄን ፡ ጠብቅ ።

፳፪ ፡ ለነፍስህም ፡ ሕይወት ፡ ይሆናሉ ፥ ለአንገትህም ፡ ሞገስ ።

፳፫ ፡ የዚያን፡ጊዜ፡መንገድህን፡ተማምነህ፡ትሄዳለህ፥ እግርህም ፡ አይሰነካከልም ።

፳፬ ፡ በተኛህ ፡ ጊዜ ፡ አትፈራም ፤ ትተኛለህ ፥ እንቅልፍህም ፡ የጣፈጠ ፡ ይሆንል ሃል ።

፳፭ ፡ ድንገት ፡ ከሚያስፈራ ፡ ነገር ፥ ከሚመጣውም ፡ ከኃጥኣን ፡ ጥፋት ፡ አትፈራም ፤

፳፮ ፡ እግዚአብሔር ፡ መታመኛህ ፡ ይሆናልና ፥ እግርህም ፡ እንዳይጠመድ ፡ ይጠብቅሃልና ።

፳፯ ፡ ለተቸገረው ፡ ሰው ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ ማድረግ ፡ አት ከልክል ፥ ልታደርግለት ፡ የሚቻልህ ፡ ሲሆን ።

፳፰ ፡ ወዳጅህን ፡— ሂድና ፡ ተመለስ ፤ ነገ ፡ እሰጥሃለሁ ፡ አትበለው ፥ በጎ ፡ ነገርን ፡ ማድረግ ፡ ሲቻልህ ።

፳፱ ፡ በወዳጅህ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ አትሥራ ፥ እርሱ ፡ ተማምኖ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ።

፴ ፡ ከሰው ፡ ጋር ፡ በከንቱ ፡ አትጣላ ፥ እርሱ ፡ ክፉ ፡ ካልሠራብህ ።

፴፩ ፡ በግፈኛ ፡ ሰው ፡ አትቅና ፥ መንገዱንም ፡ ሁሉ ፡ አትምረጥ ።

፴፪ ፡ ጠማማ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ርኩስ ፡ ነውና ፤ ወዳጅነቱ ፡ ግን ፡ ከቅኖች ፡ ጋር ፡ ነው ።

፴፫ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መርገም ፡ በኃጥእ ፡ ቤት ፡ ነው ፥ የጻድቃን ፡ ቤት ፡ ግን ፡ ይባረካል ።

፴፬ ፡ በፌዘኞች ፡ እርሱ ፡ ያፌዛል ፥ ለትሑታን ፡ ግን ፡ ሞገስን ፡ ይሰጣል ።

፴፭ ፡ ጠቢባን ፡ ክብርን ፡ ይወርሳሉ ፤ የሰነፎች ፡ ከፍታቸው ፡ ግን ፡ መዋረድ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ፡ እናንተ ፡ ልጆች ፥ የአባትን ፡ ተግሣጽ ፡ ስሙ ፥ ማስተዋልንም ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ አድምጡ ፤

፪ ፡ መልካም ፡ ትምህርትን ፡ እሰጣችኋለሁና ፤ ሕጌን ፡ አትተዉ ።

፫ ፡ እኔም ፡ አባቴን ፡ የምሰማ ፡ ልጅ ፡ ነበርሁና ፥ በእናቴም ፡ ዘንድ ፡ እወደድ ፡ ነበር ።

፬ ፡ ያስተምረኝም ፡ ነበር ፡ እንዲህም ፡ ይለኝ ፡ ነበር ፡— ልብህ ፡ ቃሌን ፡ ይቀበል ፤ ትእዛዜን ፡ ጠብቅ ፡ በሕይወትም ፡ ትኖራለህ ።

፭ ፡ ጥበብን ፡ አግኝ ፤ ማስተዋልን ፡ አግኝ ፤ አትር ሳም ፥ ከአፌም ፡ ቃል ፡ ፈቀቅ ፡ አትበል ።

፮ ፡ አትተዋት ፥ ትደግፍህማለች ፤ ውደዳት ፥ ትጠብቅህማለች ።

፯ ፡ ጥበብ ፡ ዓይነተኛ ፡ ነገር ፡ ናትና ፡ ጥበብን ፡ አግኝ ፤ ከሀብትህም ፡ ሁሉ ፡ ማስተዋልን ፡ አትርፍ ።

፰ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርጋት ፥ እርስዋም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ታደርግሃለች ፤ ብታቅፋትም ፡ ታከብርሃለች ።

፱ ፡ ለራስህ ፡ የሞገስ ፡ አክሊልን ፡ ትሰጥሃለች ፥ የተዋበ ፡ ዘውድንም ፡ ታበረክትሃለች ።

፲ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ስማ ፥ ንግግሬንም ፡ ተቀበል ፤ የሕይወትህም ፡ ዘመን ፡ ትበዛልሃለች ።

፲፩ ፡ የጥበብን ፡ መንገድ ፡ አስተማርሁህ ፤ በቀናች ፡ ጎዳና ፡ መራሁህ ።

፲፪ ፡ በሄድህ ፡ ጊዜ ፡ እርምጃህ ፡ አይጠብብም ፤ በሮጥህም ፡ ጊዜ ፡ አትሰናከልም ።

፲፫ ፡ ተግሣጽን ፡ ያዝ ፥ አትተውም ፤ ጠብቀው ፥ እርሱ ፡ ሕይወትህ ፡ ነውና ።

፲፬ ፡ በኀጥአን ፡ መንገድ ፡ አትግባ ፥ በክፉ ፡ ሰዎችም ፡ ጎዳና ፡ አትሂድ ።

፲፭ ፡ ከእርስዋ ፡ ራቅ ፥ አትሂድባትም ፤ ፈቀቅ ፡ በል ፡ ተዋትም ።

፲፮ ፡ ክፉ ፡ ካላደረጉ ፡ አይተኙምና ፥ ካላሰናከሉም ፡ እንቅልፋቸው ፡ ይወገዳልና ።

፲፯ ፡ የኃጢአትን ፡ እንጀራ ፡ ይበላሉና ፥ የግፍንም ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡ ይጠጣሉና ።

፲፰ ፡ የጻድቃን ፡ መንገድ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ንጋት ፡ ብር ሃን ፡ ነው ፥ ሙሉ ፡ ቀን ፡ እስኪሆንም ፡ ድረስ ፡ እየተጨ መረ ፡ ይበራል ።

፲፱ ፡ የኀጥኣን ፡ መንገድ ፡ እንደ ፡ ጨለማ ፡ ነው ፥ እንዴት ፡ እንደሚሰናከሉም ፡ አያውቁም ።

፳ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ንግግሬን ፡ አድምጥ ፡ ወደ ፡ ቃሌም ፡ ጆሮህን ፡ አዘንብል ።

፳፩ ፡ ከዓይንህ ፡ አታርቃት ፥ በልብህም ፡ ውስጥ ፡ ጠብቃት ።

፳፪ ፡ ለሚያገኙአት ፡ ሕይወት ፥ ለሥጋቸውም ፡ ሁሉ ፡ ፈውስ ፡ ነውና ።

፳፫ ፡ አጥብቀህ ፡ ልብህን ፡ ጠብቅ ፥ የሕይወት ፡ መውጫ ፡ ከእርሱ ፡ ነውና ።

፳፬ ፡ የአፍህን ፡ ጠማማነት ፡ ከአንተ ፡ አውጣ ፥ ሐሰተኞቹን ፡ ከንፈሮችም ፡ ከአንተ ፡ አርቅ ።

፳፭ ፡ ዓይኖችህ ፡ አቅንተው ፡ ይዩ ፥ ሽፋሽፍቶችህም ፡ በቀጥታ ፡ ይመልከቱ ።

፳፮ ፡ የእግርህን ፡ መንገድ ፡ አቅና ፥
አካሄድህም ፡ ሁሉ ፡ ይጽና ።
፳፯ ፡ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ አትበል ፤
እግርህንም ፡ ከክፉ ፡ መልስ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ ጥበቤ ፡ አድምጥ ፤
ጆሮህን ፡ ወደ ፡ ትምህርቴ ፡ መልስ ፥
፪ ፡ ጥንቃቄን ፡ ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፡
ከንፈሮችህም ፡ እውቀትን ፡ እንዲጠብቁ ።
፫ ፡ ከጋለሞታ ፡ ሴት ፡ ከንፈር ፡ ማር ፡ ይንጠባጠባልና ፥
አፍዋም ፡ ከቅቤ ፡ የለሰለሰ ፡ ነውና ፤
፬ ፡ ፍጻሜዋ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ እሬት ፡ የመረረ ፡ ነው ፥
ሁለት ፡ አፍ ፡ እንዳለው ፡ ሰይፍም ፡ የተሳለ ፡ ነው ።
፭ ፡ እግሮችዋ ፡ ወደ ፡ ሞት ፡ ይወርዳሉ ፥
አረማመድዋም ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ነው ፤
፮ ፡ የቀና ፡ የሕይወትን ፡ መንገድ ፡ አታገኝም ፤
በአካሄድዋ ፡ የተቅበዘበዘች ፡ ናት ፥ የሚታወቅም ፡ አይደለም ።

፯ ፡ አሁንም ፡ ልጆቼ ፡ ሆይ ፥ ስሙኝ ፥
ከአፌም ፡ ቃል ፡ አትራቁ ።
፰ ፡ መንገድህን ፡ ከእርስዋ ፡ አርቅ ፥
ወደ ፡ ቤትዋም ፡ ደጅ ፡ አትቅረብ ፥
፱ ፡ ክብርህ ፡ ለሌላ ፡ እንዳትሰጥ ፥
ዕድሜህም ፡ ለጨካኝ ፤
፲ ፡ ሌሎች ፡ ከሀብትህ ፡ እንዳይጠግቡ ፥
ድካምህም ፡ በባዕድ ፡ ሰው ፡ ቤት ፡ እንዳይሆን ።
፲፩ ፡ በመጨረሻም ፡ ሥጋህና ፡ ሰውነትህ ፡ በጠፉ ፡ ጊዜ ፡ ታለቅሳለህ ፥
፲፪ ፡ ትላለህም ፦ እንዴት ፡ ትምህርትን ፡ ጠላሁ ፥
ልቤም ፡ ዘለፋን ፡ ናቀ !
፲፫ ፡ የአስተማሪዎቼንም ፡ ቃል ፡ አልሰማሁም ፥
ጆሮቼንም ፡ ወደ ፡ አስተማሪዎቼ ፡ አላዘነበልሁም ።
፲፬ ፡ በማኅበርና ፡ በጉባኤ ፡ መካከል ፡
ወደ ፡ ክፉ ፡ ሁሉ ፡ ለመድረስ ፡ ጥቂት ፡ ቀረኝ ።

፲፭ ፡ ከጕድጓድህ ፡ ውኃ ፥ ከምንጭህም ፡ የሚፈልቀውን ፡ ውኃ ፡ ጠጣ ።
፲፮ ፡ ምንጮችህ ፡ ወደ ፡ ሜዳ ፥
ወንዞችህ ፡ ወደ ፡ አደባባይ ፡ ይፈስሳሉን ?
፲፯ ፡ ለአንተ ፡ ብቻ ፡ ይሁኑ ፥
ከአንተ ፡ ጋር ፡ ላሉ ፡ እንግዶችም ፡ አይሁኑ ።
፲፰ ፡ ምንጭህ ፡ ቡሩክ ፡ ይሁን ፤
ከጕብዝናህም ፡ ሚስት ፡ ጋር ፡ ደስ ፡ ይበልህ ።
፲፱ ፡ እንደ ፡ ተወደደች ፡ ዋላ ፡ እንደ ፡ ተዋበችም ፡ ሚዳቋ ፥
ጡትዋ ፡ ሁልጊዜ ፡ ታርክህ ፥
በፍቅርዋም ፡ ሁልጊዜ ፡ ጥገብ ።
፳ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ስለ ፡ ምን ፡ ጋለሞታ ፡ ሴት ፡ ትወድዳለህ ?
የሌላይቱንስ ፡ ብብት ፡ ለምን ፡ ታቅፋለህ ?
፳፩ ፡ የሰው ፡ መንገድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ነውና ፥
አካሄዱንም ፡ ሁሉ ፡ እርሱ ፡ ይመለከታልና ።
፳፪ ፡ ኀጥአንን ፡ ኃጢአቱ ፡ ታጠምደዋለች ፥
በኃጢአቱም ፡ ገመድ ፡ ይታሰራል ።
፳፫ ፡ አልተቀጣምና ፡ እርሱ ፡ ይሞታል ፤
በስንፍናውም ፡ ብዛት ፡ ይስታል ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ለጎረቤትህ ፡ ዋስ ፡ ብትሆን ፥
ስለ ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ እጅህን ፡ አጋና ፡ ብትመታ ፥
፪ ፡ በአፍህ ፡ ቃል ፡ ተጠመድህ ፤
በአፍህ ፡ ቃል ፡ ተያዝህ ።
፫ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ አድርግ ፡ ራስህንም ፡ አድን ፥
በጎረቤትህ ፡ እጅ ፡ ወድቀሃልና ፤
ፈጥነህ ፡ ሂድ ፥ ጎረቤትህንም ፡ ነዝንዘው ።
፬ ፡ ለዓይንህ ፡ እንቅልፍን ፡ ለሽፋሽፍቶችህም ፡ እንጕልቻን ፡ አትስጥ ፥
፭ ፡ እንደ ፡ ሚዳቋ ፡ ከአዳኝ ፡ እጅ ፥
እንደ ፡ ወፍም ፡ ከአጥማጅ ፡ እጅ ፡ ትድን ፡ ዘንድ ።

፮ ፡ አንተ ፡ ታካች ፥ ወደ ፡ ገብረ ፡ ጕንዳን ፡ ሂድ ፥
መንገድዋንም ፡ ተመልክተህ ፡ ጠቢብ ፡ ሁን ።
፯ ፡ አለቃና ፡ አዛዥ ፡ ገዢም ፡ ሳይኖራት ፡
፰ ፡ መብልዋን ፡ በበጋ ፡ ታሰናዳለች ፥
መኖዋንም ፡ በመከር ፡ ትሰበስባለች ።
፱ ፡ አንተ ፡ ታካች ፥ እስከ ፡ መቼ ፡ ትተኛለህ ?
ከእንቅልፍህስ ፡ መቼ ፡ ትነሣለህ ?
፲ ፡ ጥቂት ፡ ትተኛለህ ፥ ጥቂት ፡ ታንቀላፋለህ ፥
ትተኛም ፡ ዘንድ ፡ ጥቂት ፡ እጅህን ፡ ታጥፋለህ ፤
፲፩ ፡ እንግዲህ ፡ ድህነትህ ፡ እንደ ፡ ወንበዴ ፥
ችጋርህም ፡ ሰይፍ ፡ እንደ ፡ ታጠቀ ፡ ሰው ፡ ይመጣብሃል ።

፲፪ ፡ ምናምንቴ ፡ ሰው ፡ የበደለኛም ፡ ልጅ ፡
በጠማማ ፡ አፍ ፡ ይሄዳል ፤
፲፫ ፡ በዓይኑ ፡ ይጠቅሳል ፥ በእግሩ ፡ ይናገራል ፥
በጣቱ ፡ ያስተምራል ፤
፲፬ ፡ ጠማማነት ፡ በልቡ ፡ አለ ፥ ሁልጊዜም ፡ ክፋትን ፡ ያስባል ፤
ጠብንም ፡ ይዘራል ።
፲፭ ፡ ስለዚህ ፡ ጥፋቱ ፡ ድንገት ፡ ይደርስበታል ፤
ድንገት ፡ ይደቅቃል ፥ ፈውስም ፡ ከቶ ፡ የለውም ።
፲፮ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚጠላቸው ፡ ስድስት ፡ ነገሮች ፡ ናቸው ፥
ሰባትንም ፡ ነፍሱ ፡ አጥብቃ ፡ ትጸየፋቸዋለች ፤
፲፯ ፡ ትዕቢተኛ ፡ ዓይን ፥ ሐሰተኛ ፡ ምላስ ፥
ንጹሕን ፡ ደም ፡ የምታፈስስ ፡ እጅ ፥
፲፰ ፡ ክፉ ፡ አሳብን ፡ የሚያበቅል ፡ ልብ ፥
ወደ ፡ ክፉ ፡ የምትሮጥ ፡ እግር ፥
፲፱ ፡ በሐሰት ፡ የሚናገር ፡ ሐሰተኛ ፡ ምስክር ፥
በወንድማማች ፡ መካከልም ፡ ጠብን ፡ የሚዘራ ።

፳ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ የአባትህን ፡ ትእዛዝ ፡ ጠብቅ ፥

የእናትህንም፡ሕግ፡አትተው፤
፳፩ ሁልጊዜ፡በልብህ፡አኑረው፥
በአንገትህም፡እሰረው።
፳፪ ስትሄድም፡ይመራሃል፤
ስትተኛ፡ይጠብቅሃል፤
ስትነሣ፡ያነጋግርሃል።
፳፫ ትእዛዝ፡መብራት፥ሕግም፡ብርሃን፡ነውና፥
የተግሣጽም፡ዘለፋ፡የሕይወት፡መንገድ፡ነውና፥
፳፬ ከክፉ፡ሴት፡ትጠብቅህ፡ዘንድ፡
ከሌላይቱም፡ሴት፡ምላስ፡ጥፍጥንነት።
፳፭ ውበትዋን፡በልብህ፡አትመኘው፤
ሽፋሽፍትዋም፡አያጥምድህ።
፳፮ የጋለሞታ፡ዋጋ፡እስከ፡አንዲት፡እንጀራ፡ነው፤
አመንዝራም፡ሴት፡የሰውን፡ሕይወት፡ታጠምዳለች።
፳፯ በጉያው፡እሳትን፡የሚታቀፍ፥
ልብሶቹስ፡የማይቃጠሉ፡ማን፡ነው?
፳፰ በፍም፡ላይ፡የሚሄድ፥
እግሮቹስ፡የማይቃጠሉ፡ማን፡ነው?
፳፱ ወደ፡ሰው፡ሚስት፡የሚገባም፡እንዲሁ፡ነው፤
የሚነካትም፡ሁሉ፡ሳይቀጣ፡አይቀርም።
፴ ሌባ፡በተራበ፡ጊዜ፡ነፍሱን፡ሊያጠግብ፡ቢሰርቅ፡
ሰዎች፡ አይንቁትም፤
፴፩ ቢያዝም፡ሰባት፡እጥፍ፡ይከፍላል፥
በቤቱም፡ያለውን፡ሁሉ፡ይሰጣል።
፴፪ ከሴት፡ጋር፡የሚያመነዝር፡ግን፡አእምሮው፡የጐደለ፡ነው፤
እንዲሁም፡የሚያደርግ፡ነፍሱን፡ያጠፋል።
፴፫ ቍስልንና፡ውርደትን፡ያገኛል፥
ስድቡም፡አይደመሰስም።
፴፬ ቅንዓት፡ለሰው፡የቍጣ፡ትኵሳት፡ነውና፥
በበቀልም፡ቀን፡አይራራለትምና።
፴፭ እርሱም፡ምንም፡ካሣ፡አይቀበልም፥
ስጦታም፡ብታበዛለት፡አይታረቅም።

## ምዕራፍ፡፯።

፩ ልጄ፡ሆይ፥ቃሌን፡ጠብቅ፡
ትእዛዜንም፡በአንተ፡ዘንድ፡ሸሽግ።
፪ ትእዛዜን፡ጠብቅ፡በሕይወትም፡ትኖራለህ፤
ሕጌንም፡እንደ፡ዓይንህ፡ብሌን፡ጠብቅ፤
፫ በጣቶችህ፡እሰራቸው፤
በልብህ፡ጽላት፡ጻፋቸው።
፬ ጥበብን፦አንቺ፡እኅቴ፡ነሽ፡በላት፥
ማስተዋልንም፦ወዳጄ፡ብለህ፡ጥራት፥
፭ ከጋለሞታ፡ሴት፡ትጠብቅህ፡ዘንድ፥
ቃልዋን፡ካለዘበች፡ከሌላይቱ፡ሴት።

፮ በቤቴ፡መስኮት፡ሆኜ፡ወደ፡አደባባይ፡ተመለከትሁ፤
፯ ከአላዋቂዎች፡መካከል፡አስተዋልሁ፤
ከጐበዛዝትም፡መካከል፡ብላቴናውን፡አእምሮ፡ጐድሎት፡አየሁ፥
፰ በአደባባይ፡ሲሄድ፡በቤትዋም፡አቅራቢያ፡ሲያልፍ፤
የቤትዋን፡መንገድ፡ይዞ፡ወደ፡እርስዋ፡አቀና፥
፱ ማታ፡ሲመሽ፥ውድቅትም፡ሲሆን፥
በሌሊትም፡በጽኑ፡ጨለማ።
፲ እነሆ፥ሴት፡ተገናኘችው፡
የጋለሞታ፡ልብስ፡የለበሰች፥
ነፍሳትን፡ለማጥመድ፡የተዘጋጀች።
፲፩ ሁከተኛና፡አበያ፡ናት፥
እግሮችዋም፡በቤትዋ፡አይቀመጡም፤
፲፪ አንድ፡ጊዜ፡በጎዳና፥አንድ፡ጊዜ፡በአደባባይ፥
በማዕዘኑም፡ሁሉ፡ታደባለች።
፲፫ ያዘችውም፡ሳመችውም፤
ፊትዋም፡ያለ፡እፍረት፡ሆኖ፡እንዲህ፡አለችው፦
፲፬ መሥዋዕትንና፡የደኅንነት፡ቍርባንን፡ማቅረብ፡ነበረብኝ፤
ዛሬ፡ስእለቴን፡ፈጸምሁ።
፲፭ ስለዚህ፡እንድገናኝህ፥ፊትህንም፡በትጋት፡ለመሻት፡ወጥቻለሁ፥
አግኝቼሃለሁም።
፲፮ በአልጋዬ፡ላይ፡ማለፊያ፡ሰርፍ፡ዘርግቼበታለሁ፥
የግብጽንም፡ሽመልመሌ፡ለሀፍ።
፲፯ በመኝታዬ፡ከርቤንና፡ዓልሙን፡ቀረፋም፡ረጭቼበታለሁ።
፲፰ ና፥እስከ፡ነጋ፡ድረስ፡በፍቅር፡እንርካ፥
በተወደደ፡መተቃቀፍም፡ደስ፡ይበለን።
፲፱ ባለቤቴ፡በቤቱ፡የለምና፥
ወደ፡ሩቅ፡መንገድ፡ሄዶአልና፤
፳ በእጁም፡የብር፡ከረጢት፡ወስዶአል፤
ሙሉ፡ጨረቃ፡በሆነች፡ጊዜ፡ወደ፡ቤቱ፡ይመለሳል።
፳፩ በብዙ፡ጨዋታዋ፡እንዲስት፡ታደርገዋለች፤
በከንፈርዋ፡ልዝብነት፡ትጐትተዋለች።
፳፪ እርሱ፡እንዲህ፡ስቶ፡ይከተላታል፥
በሬ፡ለመታረድ፡እንዲነዳ፥
ውሻም፡ወደ፡እስራት፡እንዲሄድ፥
፳፫ ወፍ፡ወደ፡ወጥመድ፡እንደሚቸኵል፥
ለነፍሱ፡ጥፋት፡እንደሚሆን፡ሳያውቅ፥
ፍላጻ፡ጉበቱን፡እስኪሰነጥቀው፡ድረስ።

፳፬ ልጆቼ፡ሆይ፥አሁን፡እንግዲህ፡ስሙኝ፡
ወደ፡አፌም፡ቃል፡አድምጡኝ።
፳፭ ልብህ፡ወደ፡መንገድዋ፡አያዘንብል፤
በጎዳናዋ፡አትሳት።
፳፮ ወግታ፡የጣለቻቸው፡ብዙ፡ናቸውና፤
እርስዋም፡የገደለቻቸው፡እጅግ፡ብዙ፡ናቸው።
፳፯ ቤትዋ፡የሲኦል፡መንገድ፡ነው፤
ወደ፡ሞት፡ማጀት፡የሚወርድ፡ነው።

## ምዕራፍ፡፰።

፩ በውኑ፡ጥበብ፡አትጮኽምን?
ማስተዋልስ፡ድምፅዋን፡አትሰጥምን?

፪፡ በኮረብታ ፡ ላይ ፡ በመንገድ ፡ አጠገብ ፡
በጎዳና ፡ መካከል ፡ ትቆማለች ።
፫፡ በበሩ ፡ አጠገብ ፡ በከተማይቱም ፡ መግቢያ ÷
በደጁ ፡ መግቢያ ፡ ትጮኻለች ፡—
፬፡ እናንተ ፡ ሰዎች ÷ እናንተን ፡ እጠራለሁ ÷
ድምፄም ፡ ወደ ፡ ሰዎች ፡ ልጆች ፡ ነው ።
፭፡ እናንተ ፡ አላዋቂዎች ÷ ብልሃትን ፡ አስተውሉ ፤
እናንተም ፡ ሰነፎች ÷ ጥበብን ፡ በልባችሁ ፡ ያዙ ።
፮፡ የከበረች ፡ ነገርን ፡ እናገራለሁና ፡ ስሙ ፤
ከንፈሮቼም ፡ ቅን ፡ ነገርን ፡ ለመናገር ፡ ይከፈታሉ ።
፯፡ አፌ ፡ እውነትን ፡ ይናገራልና ÷
ከንፈሮቼም ፡ ክፋትን ፡ ይጸየፋሉ ።
፰፡ የአፌ ፡ ቃላት ፡ ሁሉ ፡ ጽድቅ ፡ ናቸው ፤
ጠማማ ፡ ዘወርዋራም ፡ አይደሉም ።
፱፡ እነርሱ ፡ በሚያስተውሉ ፡ ዘንድ ፡ የቀኑ ፡ ናቸው ÷
እውቀትንም ፡ ከገኙአት ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ የተስማሙ ፡ ናቸው ።
፲፡ ተግሣጼን ፡ እንጂ ፡ ብርን ፡ አትቀበሉ ÷
ከምዝምዝ ፡ ወርቅም ፡ ይልቅ ፡ እውቀትን ፡ ተቀበሉ ።
፲፩፡ ጥበብ ፡ ከቀይ ፡ ዕንቍ ፡ ትበልጣለችና ፤
የከበረ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አይተካከላትም ።
፲፪፡ እኔ ፡ ጥበብ ፡ በብልሃት ፡ ተቀምጫለሁ ÷
እውቀትንም ፡ ጥንቃቄንም ፡ አግኝቻለሁ ።
፲፫፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ክፋትን ፡ ይጠላል ፤
ትዕቢትንና ፡ እብሪትን ፡ ክፉንም ፡ መንገድ ፡
ጠማማውንም ፡ አፍ ፡ እጠላለሁ ።
፲፬፡ ምክርና ፡ መልካም ፡ ጥበብ ፡ የእኔ ፡ ነው ፤
ማስተዋል ፡ እኔ ፡ ነኝ ÷ ብርታትም ፡ አለኝ ።
፲፭፡ ነገሥታት ፡ በእኔ ፡ ይነግሣሉ ÷
ሹማምቶችም ፡ የቀናውን ፡ ነገር ፡ ይደነግጋሉ ።
፲፮፡ አለቆች ፡ በእኔ ፡ ያዝዛሉ ÷
ከቡራንና ፡ የምድር ፡ ፈራጆችም ፡ ሁሉ ።
፲፯፡ እኔ ፡ የሚወድዱኝን ፡ እወድዳለሁ ÷
ተግተው ፡ የሚሹኝም ፡ ያገኙኛል ።
፲፰፡ ብልጥግናና ፡ ክብር ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ነው ÷
ብዙ ፡ ሀብትና ፡ ጽድቅም ።
፲፱፡ ፍሬዬም ፡ ከምዝምዝ ፡ ወርቅ ፡ ይሻላል ÷
ቡቃያዬም ፡ ከተመረጠች ፡ ብር ።
፳፡ እኔ ፡ በጽድቅ ፡ መንገድ ፡ እሄዳለሁ ÷
በፍርድም ፡ ጎዳና ፡ መካከል ÷
፳፩፡ ለሚወድዱኝ ፡ ርስት ፡ አወርሳቸው ፡ ዘንድ ፡
ቤት ፡ መዛግብታቸውንም ፡ እሞላ ፡ ዘንድ ።

፳፪፡ እግዚአብሔር ፡ የመንገዱ ፡ መጀመሪያ ፡ አደረገኝ ÷
በቀድሞ ፡ ሥራው ፡ መጀመሪያ ።
፳፫፡ ከጥንቱ ፡ ከዘላለም ፡ ጀምሮ ፡ ተሾምሁ ፡
ምድር ፡ ከመፈጠርዋ ፤ አስቀድሞ ።
፳፬፡ ቀላያት ፡ ገና ፡ ሳይኖሩ ፡ እኔ ፡ ተወለድሁ ÷
የውኃ ፡ ምንጮች ፡ ገና ፡ ሳይፈልቁ ።
፳፭፡ ተራሮች ፡ ገና ፡ ሳይመሠረቱ ÷
ከኮረብቶች ፡ በፊት ፡ እኔ ፡ ተወለድሁ ÷
፳፮፡ ምድሪቱንና ፡ ሜዳውን ፡ ገና ፡ ሳይፈጥር ፡
የመጀመሪያውንም ፡ የዓለም ፡ አፈር ።
፳፯፡ ሰማዮችን ፡ በዘረጋ ፡ ጊዜ ፡ አብሬ ፡ ነበርሁ ÷
በቀላያት ፡ ፊት ፡ ክበብን ፡ በደነገገ ፡ ጊዜ ÷
፳፰፡ ደመናትን ፡ በላይ ፡ በዘጋጀ ፡ ጊዜ ÷
የቀላይን ፡ ምንጮች ፡ በጸና ፡ ጊዜ ÷
፳፱፡ ለባሕርም ፡ ዳርቻን ፡ በወሰነ ፡ ጊዜ ፡
ውኃ ፡ ከትእዛዙ ፡ እንዳያልፍ ÷
የምድርን ፡ መሠረት ፡ በመሠረተ ፡ ጊዜ ÷
፴፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ዋና ፡ ሠራተኛ ፡ ነበርሁ ፤
ዕለት ፡ ዕለት ፡ ደስ ፡ አሰኘው ፡ ነበርሁ ÷
በፊቱም ፡ ሁልጊዜ ፡ ደስ ፡ ይለኝ ፡ ነበርሁ ÷
፴፩፡ ደስታዬም ፡ በምድሩ ፡
ተድላዬም ፡ በሰው ፡ ልጆች ፡ ነበረ ።

፴፪፡ አሁንም ፡ ልጆቼ ፡ ሆይ ÷ ስሙኝ ፤
መንገዴንም ፡ የሚጠብቁ ፡ ምስጉኖች ፡ ናቸው ።
፴፫፡ ትምህርቴን ፡ ስሙ ÷ ጠቢባንም ፡ ሁኑ ÷ ቸል ፡ አትበሉትም ።
፴፬፡ የሚሰማኝ ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ፡
ዕለት ፡ ዕለት ፡ በቤቴ ፡ መግቢያ ፡ የሚተጋ ÷
የደጄንም ፡ መድረክ ፡ የሚጠብቅ ።
፴፭፡ እኔን ፡ ያገኘ ፡ ሕይወትን ፡ ያገኛልና ÷
ከእግዚአብሔርም ፡ ሞገስን ፡ ያገኛልና ።
፴፮፡ እኔን ፡ ያጣ ፡ ግን ፡ ራሱን ፡ ይጐዳል ፤
የሚጠሉኝ ፡ ሁሉ ፡ ሞትን ፡ ይወድዳሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩፡ ጥበብ ፡ ቤትዋን ፡ ሠራች ÷
ሰባቱንም ፡ ምሰሶችዋን ፡ አቆመች ።
፪፡ ፍሪዳዋን ፡ አረደች ÷ የወይን ፡ ጠጅዋን ፡ ደባለቀች ÷
ማዕድዋን ፡ አዘጋጀች ።
፫፡ ባሪያዎችዋን ፡ ልካ ፡
በከተማይቱ ፡ ከፍተኛ ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ ጠራች ፡—
፬፡ አላዋቂ ፡ የሆነ ፡ ወደዚህ ፡ ፈቀቅ ፡ ይበል ፤
አእምሮ ፡ የጐደላቸውንም ፡ እንዲህ ፡ አለች ፡—
፭፡ ኑ ÷ እንጀራዬን ፡ ብሉ ÷
የደባለቅሁትንም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ጠጡ ።
፮፡ አላዋቂነትን ፡ ትታችሁ ፡ በሕይወት ፡ ኑሩ ÷
በማስተዋልም ፡ መንገድ ፡ ሂዱ ።
፯፡ ፌዘኛን ፡ የሚገሥጽ ፡ ለራሱ ፡ ስድብን ፡ ይቀበላል ÷
ኀጥእንም ፡ የሚዘልፍ ፡ ነውርን ፡ ያገኛል ።
፰፡ ፌዘኛን ፡ አትገሥጽ ፡ እንዳይጠላህ ፤
ጠቢብን ፡ ገሥጽ ፡ ይወድድሃል ።
፱፡ ለጠቢብ ፡ ሰው ፡ ትምህርትን ፡ ስጠው ÷ ጥበብንም ፡ ያበዛል ፤
ጻድቅንም ፡ አስተምረው ÷ እውቀትንም ፡ ያበዛል ።
፲፡ የጥበብ ፡ መጀመሪያ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ነው ፤
ቅዱሱንም ፡ ማወቅ ፡ ማስተዋል ፡ ነው ።

፲፩፤ ዘመንህ ፡ በእኔ ፡ ይበዛልና ፥
የሕይወትህም ፡ ዕድሜ ፡ ይጨመርልሃልና ።
፲፪፤ ጠቢብ ፡ ብትሆን ፤ ለራስህ ፡ ጠቢብ ፡ ትሆናለህ ፥
ፌዘኛም ፡ ብትሆን ፡ ፌዘኛነትህን ፡ ለብቻህ ፡ ትሸ
ከማለህ ።

(የሚቀጥለው ፡ ከግሪክ ፡ የተጨመረ ፡ ነው ።)
ልጄ ፡ ለራስህ ፡ አዋቂ ፡ ብትሆን ፡ ለባልንጀራህም ፡
አዋቂ ፡ ትሆናለህ ፤
ለራስህ ፡ ክፉ ፡ ብትሆን ፡ ግን ፡ ክፉትን ፡ ትማራለህ ።
ሐሰትን ፡ የሚያዘጋጅ ፡ ሰው ፡ ነፋሳትን ፡ እንደሚያዘ
ጋጅ ፡ ሰው ፡ ነው ፤
የሚበርር ፡ ወፍንም ፡ እንደሚከተል ፡ ይመስላል ።
የወይኑ ፡ ቦታ ፡ መንገዱን ፡ ተወ ፤
የሚሠማራባትን ፡ መንገድ ፡ ዘንጋ ፤
ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ይሄዳል ፤
ለጥም ፡ ወደ ፡ ተሠራች ፡ አገር ፡ ይሄዳል ፤
የማያፈራ ፡ የማይጠቅም ፡ ገንዘብንም ፡ በእጁ ፡ ይሰበ
ስባል ።

፲፫፤ ሰነፍ ፡ ሴት ፡ ሁከተኛ ፡ ናት ፤
አሳብ ፡ የላትም ፥ አንዳችም ፡ አታውቅም ።
፲፬፤ በቤትዋ ፡ ደጅ ፤
በከተማይቱ ፡ ከፍተኛ ፡ ስፍራ ፡ በወንበር ፡ ላይ ፡
ትቀመጣለች ፥
፲፭፤ በመንገድ ፡ የሚያልፉትን ፡
አካሄዳቸውንም ፡ ያቀኑትን ፡ ለመጥራት ፡—
፲፮፤ አላዋቂ ፡ የሆነ ፡ ወደዚህ ፡ ፈቀቅ ፡ ይበል ፤
አእምሮ ፡ የጐደለውንም ፡ እንዲህ ፡ አለች ፡—
፲፯፤ የስርቆት ፡ ውኃ ፡ ይጣፍጣል ፥
የተሸሸገም ፡ እንጀራ ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ።
፲፰፤ ነገር ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ ሙታን ፡ ከዚያ ፡ እንዳሉ ፥
እድመኞችዋም ፡ በሲኦል ፡ ጥልቀት ፡ እንዳሉ ፡
አያውቅም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፤ የሰሎሞን ፡ ምሳሌዎች ።
ጠቢብ ፡ ልጅ ፡ አባቱን ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፤
ሰነፍ ፡ ልጅ ፡ ግን ፡ ለእናቱ ፡ ኀዘን ፡ ነው ።
፪፤ በኃጢአት ፡ የተገኘ ፡ መዝገብ ፡ ጥቅም ፡ የለውም ፤
ጽድቅ ፡ ግን ፡ ከሞት ፡ ያድናል ።
፫፤ እግዚአብሔር ፡ የጻድቁን ፡ ነፍስ ፡ አያስርብም ፤
የኀጥአንን ፡ ምኞት ፡ ግን ፡ ይገለብጣል ።
፬፤ የታከች ፡ እጅ ፡ ችግረኛ ፡ ታደርጋለች ፤
የትጉ ፡ እጅ ፡ ግን ፡ ባለጠጋ ፡ ታደርጋለች ።
፭፤ በበጋ ፡ የሚያከማች ፡ ልጅ ፡ አስተዋይ ፡ ነው ፤
በመከር ፡ የሚተኛ ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ ራሱን ፡ ያስነ
ውራል ።
፮፤ በረከት ፡ በጻድቅ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ነው ፤
የኀጥአንን ፡ አፍ ፡ ግን ፡ ግፍ ፡ ይከድነዋል ።
፯፤ የጻድቅ ፡ መታሰቢያ ፡ ለበረከት ፡ ነው ፤
የኀጥአን ፡ ስም ፡ ግን ፡ ይጠፋል ።
፰፤ በልቡ ፡ ጠቢብ ፡ የሆነ ፡ ትእዛዝን ፡ ይቀበላል ፤
በከንፈሩ ፡ የሚሰንፍ ፡ ግን ፡ ይወድቃል ።
፱፤ ያለ ፡ ነውር ፡ የሚሄድ ፡ ተማምኖ ፡ ይሄዳል ፤
መንገዱን ፡ የሚያጣምም ፡ ግን ፡ ይታወቃል ።
፲፤ በዓይኑ ፡ የሚጠቅስ ፡ መከራን ፡ ያመጣል ፤
ደፍሮ ፡ የሚገሥጽ ፡ ግን ፡ ሰላምን ፡ ያደርጋል ።
፲፩፤ የጻድቅ ፡ አፍ ፡ የሕይወት ፡ ምንጭ ፡ ናት ፤
የኀጥአንን ፡ አፍ ፡ ግን ፡ ግፍ ፡ ይከድነዋል ።
፲፪፤ ጥል ፡ ክርክርን ፡ ታስነሣለች ፤
ፍቅር ፡ ግን ፡ ኃጢአትን ፡ ሁሉ ፡ ትከድናለች ።
፲፫፤ በብልሃተኛ ፡ ከንፈር ፡ ጥበብ ፡ ትገኛለች ፤
በትር ፡ ግን ፡ አእምሮ ፡ ለጐደለው ፡ ሰው ፡ ጀርባ ፡
ነው ።
፲፬፤ ጠቢባን ፡ እውቀትን ፡ ይሸሽጋሉ ፤
የሰነፍ ፡ አፍ ፡ ግን ፡ ለጥፋት ፡ ይቀርባል ።
፲፭፤ የባለጠጋ ፡ ሀብት ፡ ለእርሱ ፡ የጸናች ፡ ከተማ ፡
ናት ፤
የድሆች ፡ ጥፋት ፡ ድህነታቸው ፡ ነው ።
፲፮፤ የጻድቅ ፡ ደመወዝ ፡ ለሕይወት ፡ ነው ፤
የኀጥእ ፡ ፍሬ ፡ ግን ፡ ለኃጢአት ፡ ነው ።
፲፯፤ ተግሣጽን ፡ የሚጠብቅ ፡ በሕይወት ፡ መንገድ ፡
ይሄዳል ፤
ዘለፋን ፡ የሚተው ፡ ግን ፡ ይስታል ።
፲፰፤ ጥልን ፡ የሚከድን ፡ ሐሰተኛ ፡ ከንፈር ፡ አለው ፤
ሐሜትንም ፡ የሚገልጥ ፡ ሰነፍ ፡ ነው ።
፲፱፤ በቃል ፡ ብዛት ፡ ውስጥ ፡ ኃጢአት ፡ ሳይኖር ፡
አይቀርም ፤
ከንፈሩን ፡ የሚገታ ፡ ግን ፡ አስተዋይ ፡ ነው ።
፳፤ የጻድቅ ፡ ምላስ ፡ የተፈተነ ፡ ብር ፡ ነው ፤
የኀጥአን ፡ ልብ ፡ ግን ፡ ምናምን ፡ ነው ።
፳፩፤ የጻድቅ ፡ ከንፈሮች ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ ይመግባሉ ፤
ሰነፎች ፡ ግን ፡ ከልባቸው ፡ ጉድለት ፡ የተነሣ ፡
ይሞታሉ ።
፳፪፤ የእግዚአብሔር ፡ በረከት ፡ ባለጠጋ ፡ ታደርጋ
ለች ፥
ኀዘንንም ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ አይጨምርም ።
፳፫፤ ክፉ ፡ ነገር ፡ ማድረግ ፡ ለሰነፍ ፡ ሰው ፡ ጨዋታ ፡
ነው ፤
እንዲሁም ፡ ጥበብ ፡ ለአስተዋይ ፡ ነው ።
፳፬፤ የኀጥእ ፡ ሰው ፡ ፍርሃት ፡ በላዩ ፡ ይመጣበታል ፥
ለጻድቃንም ፡ ምኞታቸው ፡ ትሰጣቸዋለች ።
፳፭፤ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ሲያልፍ ፡ ኀጥእ ፡ አይገኝም ፤
ጻድቅ ፡ ግን ፡ የዘላለም ፡ መሠረት ፡ ነው ።
፳፮፤ ሆምጣጤ ፡ ጥርስን ፥ ጢስም ፡ ዓይንን ፡ እንደ
ሚጐዳ ፥
እንዲሁም ፡ ታካች ፡ ለላኩት ።
፳፯፤ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ዘመንን ፡ ታረዝ
ማለች ፤
የኀጥአን ፡ ዕድሜ ፡ ግን ፡ ታጥራለች ።
፳፰፤ የጻድቃን ፡ አለኝታ ፡ ደስታ ፡ ነው ፤
የኀጥአን ፡ ተስፋ ፡ ግን ፡ ይጠፋል ።
፳፱፤ የእግዚአብሔር ፡ መንገድ ፡ ያለ ፡ ነውር ፡ ለሚ
ሄድ ፡ አምባ ፡ ነው ፥
ጥፋት ፡ ግን ፡ ክፉትን ፡ ለሚያደርጉ ።
፴፤ ጻድቃን ፡ ለዘላለም ፡ አይናወጡም ፤
ኀጥአን ፡ ግን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አይቀመጡም ።

፴፩፤ የጻድቅ ፡ አፍ ፡ ጥበብን ፡ ይናገራል ፤
ጠማማ ፡ ምላስ ፡ ግን ፡ ትቈረጣለች ።
፴፪፤ የጻድቅ ፡ ከንፈሮች ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ነገርን ፡ ያውቃሉ ፤
የኀጥኣን ፡ አፍ ፡ ግን ፡ ጠማማ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩፤ አባይ ፡ ሚዛን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አስጸያፊ ፡ ነው ፤
እውነተኛ ፡ ሚዛን ፡ ግን ፡ ደስ ፡ ያሰኘዋል ።
፪፤ ትዕቢት ፡ ከመጣች ፡ ውርደት ፡ ትመጣለች ፤
በትሑታን ፡ ዘንድ ፡ ግን ፡ ጥበብ ፡ ትገኛለች ።
፫፤ ቅኖችን ፡ ቅንነታቸው ፡ ትመራቸዋለች ፤
ወስላቶችን ፡ ግን ፡ ጠማማነታቸው ፡ ታጠፋቸዋለች ።
፬፤ በቍጣ ፡ ቀን ፡ ሀብት ፡ አትረባም ፤
ጽድቅ ፡ ግን ፡ ከሞት ፡ ታድናለች ።
፭፤ የፍጹም ፡ ሰው ፡ ጽድቁ ፡ መንገዱን ፡ ያቀናለታል ፤
ኀጥእ ፡ ግን ፡ በኃጢአቱ ፡ ይወድቃል ።
፮፤ ቅኖችን ፡ ጽድቃቸው ፡ ይታደጋቸዋል ፤
ወስላቶች ፡ ግን ፡ በምኞታቸው ፡ ይጠመዳሉ ።
፯፤ ኀጥእ ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ ተስፋው ፡ ይቈረጣል ፥
የኃያል ፡ አለኝታም ፡ ይጠፋል ።
፰፤ ጻድቅ ፡ ከጭንቀት ፡ ይድናል ፥
ኀጥእም ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ይመጣል ።
፱፤ ዝንጉ ፡ ሰው ፡ በአፉ ፡ ባልንጀራውን ፡ ያጠፋል ፤
ጻድቃን ፡ ግን ፡ በእውቀት ፡ ይድናሉ ።
፲፤ በጻድቃን ፡ ልማት ፡ ከተማ ፡ ደስ ፡ ይላታል ፥
በኀጥኣንም ፡ ጥፋት ፡ እልል ፡ ትላለች ።
፲፩፤ በቅኖች ፡ በረከት ፡ ከተማ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ትላለች ፤
በኀጥኣን ፡ አፍ ፡ ግን ፡ ትገለበጣለች ።
፲፪፤ ወዳጁን ፡ የሚንቅ ፡ እርሱ ፡ አእምሮ ፡ የጐደለው ፡ ነው ፤
አስተዋይ ፡ ግን ፡ ዝም ፡ ይላል ።
፲፫፤ ለሐሜት ፡ የሚሄድ ፡ ምሥጢሩን ፡ ይገልጣል ፤
በመንፈስ ፡ የታመነ ፡ ግን ፡ ነገሩን ፡ ይሰውራል ።
፲፬፤ መልካም ፡ ምክር ፡ ከሌለ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝብ ፡ ይወድቃል ፤
በመከሮች ፡ ብዛት ፡ ግን ፡ ደኅንነት ፡ ይሆናል ።
፲፭፤ ለማያውቅ ፡ የሚዋስ ፡ ክፉ ፡ መከራን ፡ ይቀበላል ፤
ዋስነትን ፡ የሚጠላ ፡ ግን ፡ ይድናል ።
፲፮፤ ሞገስ ፡ ያላት ፡ ሴት ፡ ክብርን ፡ ታገኛለች ፥
ሀኬተኞችም ፡ ሀብትን ፡ ያገኛሉ ።
፲፯፤ ቸር ፡ ሰው ፡ ለራሱ ፡ መልካም ፡ ያደርጋል ፤
ጨካኝ ፡ ግን ፡ ሥጋውን ፡ ይጐዳል ።
፲፰፤ የኀጥእ ፡ ሰው ፡ ሞያ ፡ ሐሰተኛ ፡ ነው ፤
ጽድቅን ፡ የሚዘራ ፡ ግን ፡ የታመነ ፡ ዋጋ ፡ አለው ።
፲፱፤ በጽድቅ ፡ የሚጸና ፡ በሕይወት ፡ ይኖራል ፤
ክፋትን ፡ የሚከተል ፡ ግን ፡ ለሞቱ ፡ ነው ።
፳፤ ልበ ፡ ጠማሞች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ አስጸያፊዎች ፡ ናቸው ፤
በመንገዳቸው ፡ ፍጹማን ፡ የሆኑ ፡ ግን ፡ የተወደዱ ፡ ናቸው ።
፳፩፤ ክፉ ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ በእጅ ፡ ሳይቀጣ ፡ አይቀርም ፤
የጻድቃን ፡ ዘር ፡ ግን ፡ ይድናል ።
፳፪፤ የወርቅ ፡ ቀለበት ፡ በእርያ ፡ አፍንጫ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥
ከጥበብ ፡ የተለየች ፡ ቆንጆ ፡ ሴትም ፡ እንዲሁ ፡ ናት ።
፳፫፤ የጻድቃን ፡ ምኞት ፡ በጎ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤
የኀጥኣን ፡ ተስፋ ፡ ግን ፡ መቅሠፍት ፡ ነው ።
፳፬፤ ያለውን ፡ የሚበትን ፡ ሰው ፡ አለ ፥ ይጨመርለታልም ፤
ያለ ፡ ቅጥ ፡ የሚነፍግ ፡ ሰውም ፡ አለ ፥ ይደኸያልም ።
፳፭፤ የምትባረክ ፡ ነፍስ ፡ ትጠግባለች ፥
የረካም ፡ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ ይረካል ።
፳፮፤ እህልን ፡ የሚያስቀር ፡ ሰው ፡ በሕዝብ ፡ ዘንድ ፡ ይረገማል ፤
በረከት ፡ ግን ፡ በሚሸጠው ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ነው ።
፳፯፤ መልካምን ፡ ተግቶ ፡ የሚሻ ፡ ደስታን ፡ ይፈልጋል ፤
ክፉን ፡ በሚፈልግ ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ ይመጣበታል ።
፳፰፤ በባለጠግነቱ ፡ የሚተማመን ፡ ሰው ፡ ይወድቃል ፤
ጻድቃን ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ቅጠል ፡ ይለመልማሉ ።
፳፱፤ ቤቱን ፡ የሚያውክ ፡ ሰው ፡ ነፋስን ፡ ይወርሳል ፥
ሰነፍም ፡ ለጠቢብ ፡ ተገዥ ፡ ይሆናል ።
፴፤ የጻድቅ ፡ ፍሬ ፡ የሕይወት ፡ ዛፍ ፡ ናት ፥
ነፍሶችንም ፡ የሚሰበስብ ፡ እርሱ ፡ ጠቢብ ፡ ነው ።
፴፩፤ እነሆ ፥ ጻድቅ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ፍዳውን ፡ የሚቀበል ፡ ከሆነ ፥
ይልቁንስ ፡ ኀጥእና ፡ ዓመፀኛ ፡ እንዴት ፡ ይሆናሉ !

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩፤ ተግሣጽን ፡ የሚወድድ ፡ እውቀትን ፡ ይወድዳል ፤
ዘለፋን ፡ የሚጠላ ፡ ግን ፡ ደንቆሮ ፡ ነው ።
፪፤ ደኅና ፡ ሰው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ሞገስን ፡ ያገኛል ፤
ተንኰለኛውን ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ይቀሥፈዋል ።
፫፤ ሰውን ፡ ዓመፃ ፡ አያጸናውም ፤
የጻድቃን ፡ ሥር ፡ ግን ፡ አይንቀሳቀስም ።
፬፤ ልባም ፡ ሴት ፡ ለባልዋ ፡ ዘውድ ፡ ናት ፤
አሳፋሪ ፡ ሴት ፡ ግን ፡ በአጥንቱ ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ ቅንቅን ፡ ናት ።
፭፤ የጻድቃን ፡ አሳብ ፡ ቅን ፡ ነው ፤
የኀጥኣን ፡ ምክር ፡ ግን ፡ ተንኰል ፡ ነው ።
፮፤ የኀጥኣን ፡ ቃል ፡ ደምን ፡ ለማፍሰስ ፡ ትሸምቃለች ፤
የቅኖች ፡ አፍ ፡ ግን ፡ ይታደጋቸዋል ።
፯፤ ኀጥኣን ፡ ይገለበጣሉ ፥ ደግሞም ፡ አይገኙም ፤
የጻድቃን ፡ ቤት ፡ ግን ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ።
፰፤ ሰው ፡ በጥበቡ ፡ ይመሰገናል ፤
ልቡ ፡ ጠማማ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ይናቃል ።
፱፤ ለራሱ ፡ ባሪያ ፡ ሆኖ ፡ የተጠቃ ፡ ሰው ፡
እንጀራ ፡ ጐድሎት ፡ ራሱን ፡ ከከበረው ፡ ሰው ፡ ይሻላል ።

፲፤ ጻድቅ ፡ ሰው ፡ ለእንስሳው ፡ ነፍስ ፡ ይራራል ፤
የኀጥአን ፡ ምሕረት ፡ ግን ፡ ጨካኝ ፡ ነው ።
፲፩፤ ምድሩን ፡ የሚሠራ ፡ ሰው ፡ እንጀራ ፡ ይጠግባል ፤
ለከንቱ ፡ ነገር ፡ የሚሮጥ ፡ ግን ፡ አእምሮ ፡ የጐደለው ፡ ነው ።
፲፪፤ የኀጥአን ፡ ፈቃድ ፡ የክፉዎች ፡ ወጥመድ ፡ ናት ፤
የጻድቃን ፡ ሥር ፡ ግን ፡ ፍሬን ፡ ያፈራል ።
፲፫፤ ክፉ ፡ ሰው ፡ በከንፈሩ ፡ ኃጢአት ፡ ይጠመዳል ፤
ጻድቅ ፡ ግን ፡ ከመከራ ፡ ያመልጣል ።
፲፬፤ የሰው ፡ ነፍስ ፡ ከአፉ ፡ ፍሬ ፡ መልካም ፡ ነገርን ፡ ትጠግባለች ÷
ሰውም ፡ እንደ ፡ እጁ ፡ ሥራ ፡ ዋጋውን ፡ ይቀበላል ።
፲፭፤ የሰነፍ ፡ መንገድ ፡ በዓይኑ ፡ የቀናች ፡ ናት ፤
ጠቢብ ፡ ግን ፡ ምክርን ፡ ይሰማል ።
፲፮፤ የሰነፍ ፡ ቍጣ ፡ ቶሎ ፡ ይታወቃል ፤
ብልህ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ነውርን ፡ ይሰውራል ።
፲፯፤ እውነተኛን ፡ ነገር ፡ የሚናገር ፡ ቅን ፡ ነገርን ፡ ያወራል ፤
የሐሰት ፡ ምስክር ፡ ግን ፡ ተንኰልን ፡ ያወራል ።
፲፰፤ እንደሚዋጋ ፡ ሰይፍ ፡ የሚለፈልፍ ፡ ሰው ፡ አለ ፤
የጠቢባን ፡ ምላስ ፡ ግን ፡ ጤና ፡ ነው ።
፲፱፤ የእውነት ፡ ከንፈር ፡ ለዘላለም ፡ ትቆማለች ፤
ውሸተኛ ፡ ምላስ ፡ ግን ፡ ለቅጽበት ፡ ነው ።
፳፤ ክፉን ፡ በሚያስቡ ፡ ልብ ፡ ውስጥ ፡ ተንኰል ፡ አለ ፤
በሰላም ፡ ለሚመክሩ ፡ ግን ፡ ደስታ ፡ አላቸው ።
፳፩፤ ጻድቅን ፡ መከራ ፡ አያገኘውም ፤
ኀጥአን ፡ ግን ፡ ክፉትን ፡ የተሞሉ ፡ ናቸው ።
፳፪፤ ውሸተኛ ፡ ከንፈር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ አስጸያፊ ፡ ነው ፤
እውነትን ፡ የሚያደርጉ ፡ ግን ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ የተወደዱ ፡ ናቸው ።
፳፫፤ ብልህ ፡ ሰው ፡ እውቀትን ፡ ይሸሽጋል ፤
የሰነፎች ፡ ልብ ፡ ግን ፡ ስንፍናን ፡ ያወራል ።
፳፬፤ የትጉ ፡ እጅ ፡ ትገዛለች ፤
የታካች ፡ እጅ ፡ ግን ፡ ትገብራለች ።
፳፭፤ ሰውን ፡ የልቡ ፡ ኀዘን ፡ ያዋርደዋል ፤
መልካም ፡ ቃል ፡ ግን ፡ ደስ ፡ ያሰኘዋል ።
፳፮፤ ጻድቅ ፡ ለባልንጀራው ፡ መንገድን ፡ ያሳያል ፤
የኀጥአን ፡ መንገድ ፡ ግን ፡ ታስታቸዋለች ።
፳፯፤ ታካች ፡ ሰው ፡ አደን ፡ ምንም ፡ አያድንም ፤
ለሰው ፡ የከበረ ፡ ሀብት ፡ ትጋት ፡ ነው ።
፳፰፤ በጽድቅ ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ ሕይወት ፡ አለ ፡
በጎዳናዋም ፡ ሞት ፡ የለም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩፤ ባለ ፡ አእምሮ ፡ ልጅ ፡ የአባቱን ፡ ተግሣጽ ፡ ይሰማል ፤
ፌዘኛ ፡ ግን ፡ ተግሣጽን ፡ አይሰማም ።
፪፤ ሰው ፡ ከአፉ ፡ ፍሬ ፡ መልካምን ፡ ይበላል ፤
የዓመፀኞች ፡ ነፍስ ፡ ግን ፡ ግፍን ፡ ትሻለች ።
፫፤ አፉን ፡ የሚጠብቅ ፡ ነፍሱን ፡ ይጠብቃል ፤
ከንፈሩን ፡ የሚያሞጠሙጥ ፡ ግን ፡ ጥፋት ፡ ያገኘዋል ።
፬፤ የታካች ፡ ሰው ፡ ነፍስ ፡ ትመኛለች ፤ አንዳችም ፡ አታገኝም ፤
የትጉ ፡ ነፍስ ፡ ግን ፡ ትጠግባለች ።
፭፤ ጻድቅ ፡ ሐሰትን ፡ ይጠላል ፤
ኀጥእ ፡ ግን ፡ ያሳፍራል ፡ ያስነውራልም ።
፮፤ በመንገዱ ፡ ያለ ፡ ነውር ፡ የሚሄደውን ፡ ጽድቅ ፡ ይጠብቀዋል ፤
ኃጢአት ፡ ግን ፡ ኃጢአተኛውን ፡ ይጥለዋል ።
፯፤ ራሱን ፡ ባለጠጋ ፡ የሚያስመስል ፡ ሰው ፡ አለ ÷ ነገር ፡ ግን ፡ አንዳች ፡ የለውም ፤
ራሱን ፡ ድሀ ፡ የሚያስመስል ፡ አለ ÷ ነገር ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ባለጠግነት ፡ አለው ።
፰፤ ለሰው ፡ ነፍስ ፡ ቤዛው ፡ ሀብቱ ፡ ነው ፤
ድሀ ፡ ግን ፡ ተግሣጽን ፡ አይሰማም ።
፱፤ ሁልጊዜ ፡ ለጻድቃን ፡ ብርሃን ፡ ነው ፤
የኀጥአን ፡ መብራት ፡ ግን ፡ ይጠፋል ።
፲፤ በትዕቢት ፡ ጠብ ፡ ብቻ ፡ ይሆናል ፤
ጥበብ ፡ ግን ፡ ምክርን ፡ በሚቀበሉ ፡ ዘንድ ፡ ናት ።
፲፩፤ በችኰላ ፡ የምትከማች ፡ ሀብት ፡ ትጐድላለች ፤
ጥቂት ፡ በጥቂት ፡ የተከማቸች ፡ ግን ፡ ትበዛለች ።
፲፪፤ የምትዘገይ ፡ ተስፋ ፡ ልብን ፡ ታሳዝናለች ፤
የተገኘች ፡ ፈቃድ ፡ ግን ፡ የሕይወት ፡ ዛፍ ፡ ናት ።
፲፫፤ ትእዛዝን ፡ የሚያቃልል ፡ በትእዛዝ ፡ ተይዞ ፡ ይጠፋል ፤
ትእዛዝን ፡ የሚፈራ ፡ ግን ፡ በደኅንነት ፡ ይኖራል ።
፲፬፤ ሰው ፡ ከሞት ፡ ወጥመድ ፡ ያመልጥ ፡ ዘንድ ፡
የጠቢብ ፡ ሰው ፡ ትምህርት ፡ የሕይወት ፡ ምንጭ ፡ ነው ።
፲፭፤ መልካም ፡ እውቀት ፡ ሞገስን ፡ ይሰጣል ፤
የወስላቶች ፡ መንገድ ፡ ግን ፡ ሸካራ ፡ ናት ።
፲፮፤ ብልህ ፡ ሁሉ ፡ በእውቀት ፡ ይሠራል ፤
ሰነፍ ፡ ግን ፡ ስንፍናውን ፡ ይገልጣል ።
፲፯፤ መጥፎ ፡ መልእክተኛ ፡ በክፉ ፡ ላይ ፡ ይወድቃል ፤
የታመነ ፡ መልእክተኛ ፡ ግን ፡ ፈውስ ፡ ነው ።
፲፰፤ ድህነትና ፡ ነውር ፡ ተግሣጽን ፡ ቸል ፡ ለሚሉ ፡ ነው ፤
ዘለፋን ፡ የሚሰማ ፡ ግን ፡ ይከብራል ።
፲፱፤ የተፈጸመች ፡ ፈቃድ ፡ ሰውነትን ፡ ደስ ፡ ታሰኛለች ፤
ሰነፎች ፡ ግን ፡ ከክፉ ፡ መራቅን ፡ ይጸየፋሉ ።
፳፤ ከጠቢባን ፡ ጋር ፡ የሚሄድ ፡ ጠቢብ ፡ ይሆናል ፤
የሰነፎች ፡ ባልንጀራ ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ መከራን ፡ ይቀበላል ።
፳፩፤ ክፉ ፡ ነገር ፡ ኃጢአተኞችን ፡ ያሳድዳቸዋል ፤
ጻድቃን ፡ ግን ፡ መልካሙን ፡ ዋጋ ፡ ይቀበላሉ ።
፳፪፤ ጻድቅ ፡ ሰው ፡ ለልጅ ፡ ልጆቹ ፡ ያወርሳል ፤
የኃጢአተኛ ፡ ብልጥግና ፡ ግን ፡ ለጻድቅ ፡ ትጠበቃለች ።
፳፫፤ በድሆች ፡ እርሻ ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ሲሳይ ፡ አለ ፤
ከፍርድ ፡ መጕደል ፡ የተነሣ ፡ ግን ፡ ይጠፋል ።
፳፬፤ በበትር ፡ ከመምታት ፡ የሚራራ ፡ ሰው ፡ ልጁን ፡ ይጠላል ፤
ልጁን ፡ የሚወድድ ፡ ግን ፡ ተግቶ ፡ ይገሥጸዋል ።

፳፭፤ ጻድቅ፡ሰውነቱ፡እስክትጠግብ፡ድረስ፡ይበላል፤
የኀጥአን፡ሆድ፡ግን፡ይራብል።

## ምዕራፍ፡፲፬።

፩፤ ብልሃተኛ፡ሴት፡ቤትዋን፡ትሠራለች፤
ሰነፍ፡ሴት፡ግን፡በእጅዋ፡ታፈርሰዋለች።
፪፤ በቅን፡የሚሄድ፡ሰው፡እግዚአብሔርን፡ይፈራል፤
መንገዱን፡የሚያጣምም፡ግን፡ይንቀዋል።
፫፤ በሰነፍ፡አፍ፡የትዕቢት፡በትር፡አለ፤
የጠቢባን፡ከንፈር፡ግን፡ትጠብቃቸዋለች።
፬፤ በሬ፡በሌለበት፡ስፍራ፡እህል፡አይገኝም፤
ብዙ፡ሲሳይ፡ግን፡በበሬዎች፡ኃይል፡ነው።
፭፤ የታመነ፡ምስክር፡አይዋሽም፤
የሐሰት፡ምስክር፡ግን፡በሐሰት፡ይናገራል።
፮፤ ፌዘኛ፡ሰው፡ጥበብን፡ይፈልጋል፡አያገኛትም፤
ለአስተዋይ፡ግን፡እውቀትን፡ማግኘት፡አያስቸግረውም።
፯፤ ከሰነፍ፡ሰው፡ፊት፡ራቅ፥
በእርሱ፡ዘንድ፡የእውቀትን፡ከንፈር፡አታገኝምና።
፰፤ የብልህ፡ሰው፡ጥበብ፡መንገዱን፡ያስተውል፡ዘንድ፡ነው፤
የሰነፎች፡ስንፍና፡ግን፡ሽንገላ፡ነው።
፱፤ ሰነፍ፡በኃጢአት፡ያፌዛል፤
በቅኖች፡መካከል፡ግን፡ቸርነት፡አለች።
፲፤ የራሱን፡ኀዘን፡ልብ፡ያውቃል፤
ከደስታውም፡ጋር፡ሌላ፡ሰው፡አይገናኝም።
፲፩፤ የኀጥአን፡ቤት፡ይፈርሳል፤
የቅኖች፡ማደሪያ፡ግን፡ያብባል።
፲፪፤ ለሰው፡ቅን፡የምትመስል፡መንገድ፡አለች፤
ፍጻሜዋ፡ግን፡የሞት፡መንገድ፡ነው።
፲፫፤ በሳቅ፡ደግሞ፡ልብ፡ያዝናል፥
የደስታም፡ፍጻሜ፡ልቅሶ፡ነው።
፲፬፤ ልቡን፡ከጽድቅ፡የሚመልስ፡ሰው፡ከመንገዱ፡ፍሬ፡ይጠግባል፥
ጻድቅም፡ሰው፡ደግሞ፡በራሱ።
፲፭፤ የዋህ፡ቃልን፡ሁሉ፡ያምናል፤
ብልህ፡ግን፡አካሄዱን፡ይመለከታል።
፲፮፤ ጠቢብ፡ሰው፡ይፈራል፡ከክፉም፡ይሸሻል፤
ሰነፍ፡ግን፡ራሱን፡ታምኖ፡ይኰራል።
፲፯፤ ቍጡ፡ሰው፡በስንፍና፡ይሠራል፤
አስተዋይ፡ግን፡ይታገሣል።
፲፰፤ አላዋቂዎች፡ሰዎች፡ስንፍናን፡ይወርሳሉ፤
ብልሆች፡ግን፡እውቀትን፡እንደ፡ዘውድ፡ይጭናሉ።
፲፱፤ ኃጢአተኞች፡በደጎች፡ፊት፡ይጐነበሳሉ፥
ኀጥአንም፡በጻድቃን፡በር።
፳፤ ድሀ፡በባልንጀራው፡ዘንድ፡የተጠላ፡ነው፤
የባለጠጋ፡ወዳጆች፡ግን፡ብዙዎች፡ናቸው።
፳፩፤ ባልንጀራውን፡የሚንቅ፡ይበድላል፤
ለድሀ፡ግን፡የሚራራ፡ምስጉን፡ነው።
፳፪፤ ክፉ፡የሚያደርጉ፡ይስታሉ፤
ምሕረትና፡እውነት፡ግን፡መልካምን፡ለሚያደርጉ፡ናቸው።
፳፫፤ በድካም፡ሁሉ፡ልምላሜ፡ይገኛል፤
ብዙ፡ነገር፡በሚናገር፡ከንፈር፡ግን፡ድህነት፡ብቻ፡አለ።
፳፬፤ የጠቢባን፡ዘውድ፡ባለጠግነታቸው፡ነው፤
የሰነፎች፡ስንፍና፡ግን፡ስንፍና፡ነው።
፳፭፤ እውነተኛ፡ምስክር፡ነፍሶችን፡ያድናል፤
በሐሰት፡የሚናገር፡ግን፡ሸንጋይ፡ነው።
፳፮፤ እግዚአብሔርን፡ለሚፈራ፡ጠንካራ፡መታመን፡አለው፥
ለልጆቹም፡መጠጊያ፡ይኖራል።
፳፯፤ ሰው፡ከሞት፡ወጥመድ፡ያመልጥ፡ዘንድ፡
እግዚአብሔርን፡መፍራት፡የሕይወት፡ምንጭ፡ነው።
፳፰፤ የንጉሥ፡ክብር፡በሕዝብ፡ብዛት፡ነው፤
በሰው፡ጥቂትነት፡ግን፡የገዥ፡ጥፋት፡አለ።
፳፱፤ ለትዕግሥተኛ፡ሰው፡ብዙ፡ማስተዋል፡አለው፤
ቍጡ፡ግን፡ስንፍናውን፡ከፍ፡ከፍ፡ያደርጋል።
፴፤ ትሑት፡ልብ፡የሥጋ፡ሕይወት፡ነው፤
ቅንዓት፡ግን፡አጥንትን፡ያነቅዛል።
፴፩፤ ድሀን፡የሚያስጨንቅ፡ፈጣሪውን፡ይሰድባል፤
ለድሀ፡ምሕረትን፡የሚያደርግ፡ግን፡ያከብረዋል።
፴፪፤ ኀጥእ፡በክፋቱ፡ይደፋል፤
ጻድቅ፡ግን፡በእውነቱ፡ይታመናል።
፴፫፤ በአዋቂ፡ልብ፡ጥበብ፡ትቀመጣለች፤
በሰነፎች፡ውስጥ፡ግን፡አትታወቅም።
፴፬፤ ጽድቅ፡ሕዝብን፡ከፍ፡ከፍ፡ታደርጋለች፤
ኃጢአት፡ግን፡ሕዝብን፡ታስነውራለች።
፴፭፤ አስተዋይ፡አገልጋይ፡በንጉሥ፡ዘንድ፡ይወደዳል፤
በሚያሳፍር፡ላይ፡ግን፡ቍጣው፡ይሆናል።

## ምዕራፍ፡፲፭።

፩፤ የለዘበች፡መልስ፡ቍጣን፡ትመልሳለች፤
ሸካራ፡ቃል፡ግን፡ቍጣን፡ታስነሣለች።
፪፤ የጠቢባን፡ምላስ፡እውቀትን፡ያሳምራል፤
የሰነፎች፡አፍ፡ግን፡ስንፍናን፡ያፈልቃል።
፫፤ የእግዚአብሔር፡ዓይኖች፡በስፍራ፡ሁሉ፡ናቸው፤
ክፉዎችንና፡ደጎችን፡ይመለከታሉ።
፬፤ ፈዋሽ፡ምላስ፡የሕይወት፡ዛፍ፡ነው፤
የጠማማ፡ምላስ፡ግን፡ነፍስን፡ይሰብራል።
፭፤ ሰነፍ፡የአባቱን፡ተግሣጽ፡ይንቃል፤
ዘለፋን፡የሚቀበል፡ግን፡አእምሮው፡የበዛ፡ነው።
፮፤ በጻድቅ፡ሰው፡ቤት፡ብዙ፡ኃይል፡አለ፤
የኀጥእ፡ሰው፡መዝገብ፡ግን፡ሁከት፡ነው።
፯፤ የጠቢባን፡ከንፈር፡እውቀትን፡ትዘራለች፤
የሰነፎች፡ልብ፡ግን፡እንዲህ፡አይደለም።
፰፤ የኀጥአን፡መሥዋዕት፡በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡አስጸያፊ፡ነው፤

የቅኖች ፡ ጸሎት ፡ ግን ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ የተወደደ ፡ ነው ።
፱፤ የኀጥአን ፡ መንገድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ አስጸያፊ ፡ ነው ፤
እርሱ ፡ ግን ፡ ጽድቅን ፡ የሚከተል ፡ ይወድዳል ።
፲፤ ክፉ ፡ መቅሠፍት ፡ መንገድን ፡ በተወ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ይመጣል ፥
ዘለፋንም ፡ የሚጠላ ፡ ይሞታል ።
፲፩፤ ሲኦልና ፡ ጥፋት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የታወቁ ፡ ናቸው ፤
ይልቁንም ፡ የሰዎች ፡ ልብ ፡ የታወቀ ፡ ነው ።
፲፪፤ ፌዘኛ ፡ ሰው ፡ የሚዘልፈውን ፡ አይወድድም ፥
ወደ ፡ ጠቢባንም ፡ አይሄድም ።
፲፫፤ ደስ ፡ ያለው ፡ ልብ ፡ ፊትን ፡ ያበራል ፤
በልብ ፡ ኀዘን ፡ ግን ፡ ነፍስ ፡ ትሰበራለች ።
፲፬፤ የአዋቂ ፡ ልብ ፡ እውቀትን ፡ ይፈልጋል ፤
የሰነፎች ፡ አፍ ፡ ግን ፡ በስንፍና ፡ ይሰማራል ።
፲፭፤ ልቡ ፡ የሚያዝን ፡ ሰው ፡ ዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ የከፉች ፡ ናት ፤
የልብ ፡ ደስታ ፡ ግን ፡ ሁልጊዜ ፡ እንደ ፡ ግብዣ ፡ ነው ።
፲፮፤ እግዚአብሔርን ፡ ከመፍራት ፡ ጋር ፡ ያለ ፡ ጥቂት ፡ ነገር ፡
ሁከት ፡ ካለበት ፡ ከብዙ ፡ መዝገብ ፡ ይሻላል ።
፲፯፤ የጕመን ፡ ወጥ ፡ በፍቅር ፡ መብላት ፡
የሰባ ፡ፍሪዳን ፡ ጥል ፡ ባለበት ፡ ዘንድ ፡ ከመብላት ፡ ይሻላል ።
፲፰፤ ቍጡ ፡ ሰው ፡ ጠብን ፡ ያነሣሣል ፤
ትዕግሥተኛ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ጸጥ ፡ ያሰኘዋል ።
፲፱፤ የታካች ፡ መንገድ ፡ እንደ ፡ እሾህ ፡ አጥር ፡ ናት ፤
የጻድቃን ፡ መንገድ ፡ ግን ፡ የተደለደለች ፡ ናት ።
፳፤ ጠቢብ ፡ ልጅ ፡ አባቱን ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፤
ሰነፍ ፡ ልጅ ፡ ግን ፡ እናቱን ፡ ይንቃል ።
፳፩፤ ልብ ፡ ለሌለው ፡ ሰው ፡ ስንፍና ፡ ደስታ ፡ ናት ፤
አስተዋይ ፡ ግን ፡ አካሄዱን ፡ ያቀናል ።
፳፪፤ ምክር ፡ ከሌለች ፡ ዘንድ ፡ የታሰበው ፡ ሳይሳካ ፡ ይቀራል ፤
መካሮች ፡ በበዙበት ፡ ዘንድ ፡ ግን ፡ ይጸናል ።
፳፫፤ ሰው ፡ በአፉ ፡ መልስ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤
ቃልም ፡ በጊዜው ፡ ምንኛ ፡ መልካም ፡ ነው !
፳፬፤ በታች ፡ ካለው ፡ ከሲኦል ፡ ያመልጥ ፡ ዘንድ ፡
የሕይወት ፡ መንገድ ፡ አስተዋዩን ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ይወስደዋል ።
፳፭፤ እግዚአብሔር ፡ የትዕቢተኞችን ፡ ቤት ፡ ይነቅላል ፤
የባልቴትን ፡ ዳርቻ ፡ ግን ፡ ያጸናል ።
፳፮፤ የበደለኛ ፡ አሳብ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ አስጸያፊ ፡ ናት ፤
ያማረ ፡ ቃል ፡ ግን ፡ ጥሩ ፡ ነው ።
፳፯፤ ትርፍ ፡ ለማግኘት ፡ የሚሳሳ ፡ ሰው ፡ የራሱን ፡ ቤት ፡ ያውካል ፤
መማለጃን ፡ የሚጠላ ፡ ግን ፡ በሕይወት ፡ ይኖራል ።
፳፰፤ የጻድቅ ፡ ልብ ፡ መልሱን ፡ ያስባል ፤
የኀጥአን ፡ አፍ ፡ ግን ፡ ክፋትን ፡ ያፈልቃል ።
፳፱፤ እግዚአብሔር ፡ ከኀጥአን ፡ ይርቃል ፤
የጻድቃንን ፡ ጸሎት ፡ ግን ፡ ይሰማል ።
፴፤ የዓይን ፡ ብርሃን ፡ ልብን ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፥
መልካም ፡ ወሬም ፡ አጥንትን ፡ ያለመልማል ።
፴፩፤ የሕይወትን ፡ ተግሣጽ ፡ የሚሰማ ፡ ጆሮ ፡
በጠቢባን ፡ መካከል ፡ ይኖራል ።
፴፪፤ ተግሣጽን ፡ ቸል ፡ የሚል ፡ የራሱን ፡ ነፍስ ፡ ይንቃል ፤
ዘለፋን ፡ የሚሰማ ፡ ግን ፡ አእምሮ ፡ ያገኛል ።
፴፫፤ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ የጥበብ ፡ ትምህርት ፡ ነው ፤
ትሕትናም ፡ ክብረትን ፡ ትቀድማለች ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩፤ የልብ ፡ መዘጋጀት ፡ ከሰው ፡ ነው ፤
የምላስ ፡ መልስ ፡ ግን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
፪፤ የሰው ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ በዓይኖቹ ፡ ፊት ፡ ንጹሕ ፡ ነው ፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ መንፈስን ፡ ይመዝናል ።
፫፤ ሥራህን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አደራ ፡ ስጥ ፥
አሳብህም ፡ ትጸናለች ።
፬፤ እግዚአብሔር ፡ ሁሉን ፡ ለእርሱ ፡ ለራሱ ፡ ፈጠረ ፥
ኀጥእን ፡ ደግሞ ፡ ለክፉ ፡ ቀን ።
፭፤ በልቡ ፡ የታበየ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ርኩስ ፡ ነው ፥
እጅ ፡ በእጅም ፡ ሳይቀጣ ፡ አይቀርም ።
፮፤ በምሕረትና ፡ በእውነት ፡ ኃጢአት ፡ ትሰረያለች ፥
እግዚአብሔርንም ፡ በመፍራት ፡ ሰው ፡ ከክፋት ፡ ይመለሳል ።
፯፤ የሰው ፡ አካሄድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ ያሰኘው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
በእርሱና ፡ በጠላቶቹ ፡ መካከል ፡ ስንኳ ፡ ሰላምን ፡ ያደርጋል ።
፰፤ በጽድቅ ፡ የሚገኝ ፡ ጥቂት ፡ ነገር ፡
በዓመፅ ፡ ከሚገኝ ፡ ከብዙ ፡ ትርፍ ፡ ይሻላል ።
፱፤ የሰው ፡ ልብ ፡ መንገዱን ፡ ያዘጋጃል ፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ አካሄዱን ፡ ያቀናለታል ።
፲፤ የእግዚአብሔር ፡ ብይን ፡ በንጉሥ ፡ አፍ ፡ ነው ፥
አፉም ፡ በፍርድ ፡ አይስትም ።
፲፩፤ እውነተኛ ፡ ሚዛንና ፡ መመዘኛ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ናቸው ፤
የከረጢት ፡ መመዘኛዎች ፡ ሁሉ ፡ የእርሱ ፡ ሥራ ፡ ናቸው ።
፲፪፤ ግፍን ፡ መሥራት ፡ በንጉሥ ፡ ዘንድ ፡ ጸያፍ ፡ ነገር ፡ ነው ፥
ዙፋን ፡ በጽድቅ ፡ ይጸናልና ።
፲፫፤ የጽድቅ ፡ ከንፈር ፡ የነገሥታት ፡ ደስታ ፡ ናት ፥
በቅን ፡ የሚናገር ፡ እርሱንም ፡ ይወድዱታል ።
፲፬፤ የንጉሥ ፡ ቍጣ ፡ እንደ ፡ ሞት ፡ መልእክተኛ ፡ ነው ፤
ጠቢብ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ያቈላምጠዋል ።
፲፭፤ በንጉሥ ፡ ፊት ፡ ብርሃን ፡ ዘንድ ፡ ሕይወት ፡ አለ ፥
መልካም ፡ ፈቃዱም ፡ እንደ ፡ በልግ ፡ ዝናብ ፡ ደመና ፡ ነው ።

፲፮፤ ጥበብን ፡ ማግኘት ፡ ምንኛ ፡ ከወርቅ ፡ ይሻላል ፤
ማስተዋልንም ፡ ማግኘት ፡ ከብር ፡ ይልቅ ፡ የሚመረጥ ፡ ነው ።
፲፯፤ የቅኖች ፡ መንገድ ፡ ከክፉት ፡ መራቅ ፡ ነው ፤
መንገዱን ፡ የሚጠብቅ ፡ ነፍሱን ፡ ይጠብቃታል ።
፲፰፤ ትዕቢት ፡ ጥፋትን ፥
ኵሩ ፡ መንፈስም ፡ ውድቀትን ፡ ይቀድማል ።
፲፱፤ ከዕቡያን ፡ ጋር ፡ ምርኮ ፡ ከመካፈል ፡
ከትሑታን ፡ ጋር ፡ በተዋረደ ፡ መንፈስ ፡ መሆን ፡ ይሻላል ።
፳፤ ቃልን ፡ የሚያዳምጥ ፡ መልካም ፡ ነገርን ፡ ያገኛል ፤
በእግዚአብሔር ፡ የታመነ ፡ ምስጉን ፡ ነው ።
፳፩፤ ልቡ ፡ ጠቢብ ፡ የሆነ ፡ አስተዋይ ፡ ይባላል ፥
በከንፈሩም ፡ ጣፋጭ ፡ የሆነ ፡ ትምህርትን ፡ ያበዛል ።
፳፪፤ ገንዘብ ፡ ላደረገው ፡ ሰው ፡ እውቀት ፡ የሕይወት ፡ ምንጭ ፡ ነው ፤
ስንፍና ፡ ግን ፡ የሰነፎች ፡ ቅጣት ፡ ነው ።
፳፫፤ የጠቢብ ፡ ልብ ፡ አፉን ፡ ያስተምራል ፥
ለከንፈሩም ፡ ትምህርትን ፡ ይጨምራል ።
፳፬፤ ያማረ ፡ ቃል ፡ የማር ፡ ወለላ ፡ ነው ፤
ለነፍስ ፡ ጣፋጭ ፡ ለአጥንትም ፡ ጤና ፡ ነው ።
፳፭፤ ለሰው ፡ ቅን ፡ የምትመስል ፡ መንገድ ፡ አለች ፤
ፍጻሜዋ ፡ ግን ፡ የሞት ፡ መንገድ ፡ ነው ።
፳፮፤ የሠራተኛ ፡ ራብ ፡ ለእርሱ ፡ ይሠራል ፥
አፉ ፡ ይጐተጕተዋልና ።
፳፯፤ ምናምንቴ ፡ ሰው ፡ ክፋትን ፡ ይምሳል ፥
በከንፈሩም ፡ የሚቃጠል ፡ እሳት ፡ አለ ።
፳፰፤ ጠማማ ፡ ሰው ፡ ጥልን ፡ ይዘራል ፤
ጆሮ ፡ ጠቢ ፡ ሰው ፡ የተማመኑትን ፡ ወዳጆች ፡ ይለያያል ።
፳፱፤ ግፈኛ ፡ ሰው ፡ ወዳጁን ፡ ያባብላል ፥
መልካምም ፡ ወዳይደለ ፡ መንገድ ፡ ይመራዋል ።
፴፤ ዓይኑን ፡ የሚዘጋ ፡ ጠማማ ፡ አሳብን ፡ ያስባል ፤
ከንፈሩን ፡ የሚነክስ ፡ ክፋትን ፡ ይፈጽማል ።
፴፩፤ የሸበተ ፡ ጠጕር ፡ የክብር ፡ ዘውድ ፡ ነው ፥
እርሱም ፡ በጽድቅ ፡ መንገድ ፡ ይገኛል ።
፴፪፤ ትዕግሥተኛ ፡ ሰው ፡ ከኃያል ፡ ሰው ፡ ይሻላል ፥
በመንፈሱም ፡ ላይ ፡ የሚገዛ ፡ ከተማ ፡ ከሚወስድ ፡ ይበልጣል ።
፴፫፤ ዕጣ ፡ በኵያ ፡ ይጣላል ፤
መደብዋ ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩፤ ጥል ፡ ባለበት ፡ ዘንድ ፡ እርድ ፡ ከሞላበት ፡ ቤት ፡
በጸጥታ ፡ ደረቅ ፡ ቍራሽ ፡ ይሻላል ።
፪፤ አስተዋይ ፡ ባሪያ ፡ ነውረኛውን ፡ ልጅ ፡ ይገዛል ፥
በወንድማማች ፡ መከከልም ፡ ርስትን ፡ ይከፈላል ።
፫፤ ማቅለጫ ፡ ለብር ፥ ከውር ፡ ለወርቅ ፡ ነው ፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ልብን ፡ ይፈትናል ።
፬፤ ክፉ ፡ ሰው ፡ የበደለኛን ፡ ከንፈር ፡ ይሰማል ፤
ሐሰተኛም ፡ ወደ ፡ ተንኰለኛ ፡ ምላስ ፡ ያደምጣል ።
፭፤ በድሀ ፡ የሚያላግጥ ፡ ፈጣሪውን ፡ ይሰድባል ፤
በጥፋትም ፡ ደስ ፡ የሚለው ፡ ሳይቀጣ ፡ አይቀርም ።
፮፤ የሽማግሌዎች ፡ አክሊል ፡ የልጅ ፡ ልጆች ፡ ናቸው ፤
የልጆችም ፡ ክብር ፡ አባቶቻቸው ፡ ናቸው ።
፯፤ ለሰነፍ ፡ የኵራት ፡ አነጋገር ፡ አይገባውም ፤
ይልቁንም ፡ ሐሰተኛ ፡ ከንፈር ፡ ለመኰንን ፡ አይገባውም ።
፰፤ ገንዘብ ፡ በደረገው ፡ ፊት ፡ መማለጃ ፡ እንደ ፡ ተዋበ ፡ ዕንቍ ፡ ነው ፥
ወደ ፡ ዘረበትም ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ ሥራውን ፡ ያቀናል ።
፱፤ ኃጢአትን ፡ የሚከድን ፡ ሰው ፡ ፍቅርን ፡ ይሻል ፤
ነገርን ፡ የሚደጋግም ፡ ግን ፡ የተማመኑትን ፡ ወዳጆቹን ፡ ይለያያል ።
፲፤ መቶ ፡ ግርፋት ፡ በሰነፍ ፡ ጠልቆ ፡ ከሚገባ ፡ ይልቅ ፡
ተግሣጽ ፡ በአስተዋይ ፡ ሰው ፡ ጠልቆ ፡ ወደ ፡ ልቡ ፡ ይገባል ።
፲፩፤ ክፉ ፡ ሰው ፡ ዓመፃን ፡ ብቻ ፡ ይሻል ፤
ስለዚህ ፡ ጨካኝ ፡ መልአክ ፡ ይላክበታል ።
፲፪፤ ሰነፍን ፡ በስንፍናው ፡ ከመገናኘት ፡
ልጆችዋ ፡ የተነጠቁባትን ፡ ድብ ፡ መገናኘት ፡ ይሻላል ።
፲፫፤ በመልካም ፡ ፋንታ ፡ ክፋን ፡ የሚመልስ ፥
ክፉ ፡ ነገር ፡ ከቤቱ ፡ አትርቅም ።
፲፬፤ የጠብ ፡ መጀመሪያ ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ አፈሳሰስ ፡ ነው ፤
ስለዚህ ፡ ጠብ ፡ ሳይበረታ ፡ አንተ ፡ ክርክርን ፡ ተው ።
፲፭፤ ኀጥኡን ፡ የሚያጸድቅና ፡ በጻድቁ ፡ ላይ ፡ የሚፈርድ ፥
ሁለቱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ አስጸያፊዎች ፡ ናቸው ።
፲፮፤ በሰነፍ ፡ እጅ ፡ የጥበብ ፡ መግዣ ፡ ገንዘብ ፡ መኖሩ ፡ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
ጥበብን ፡ ይገዛ ፡ ዘንድ ፡ አእምሮ ፡ የለውምና ።
፲፯፤ ወዳጅ ፡ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ ይወድዳል ፤
ወንድምም ፡ ለመከራ ፡ ይወለዳል ።
፲፰፤ አእምሮ ፡ የጐደለው ፡ ሰው ፡ አጋና ፡ ይመታል ፥
በባልንጀራውም ፡ ፊት ፡ ይዋሳል ።
፲፱፤ ዓመፃን ፡ የሚወድድ ፡ ክርክርን ፡ ይወድዳል ፤
ደጁንም ፡ ዘለግ ፡ የሚያደርግ ፡ ውድቀትን ፡ ይሻል ።
፳፤ ጠማማ ፡ ልብ ፡ ያለው ፡ መልካምን ፡ አያገኝም ፥
ምላሱንም ፡ የሚገለብጥ ፡ በክፉ ፡ ላይ ፡ ይወድቃል ።
፳፩፤ ሰነፍን ፡ የሚወልድ ፡ ኀዘን ፡ ይሆንበታል ፥
የደንቆሮ ፡ ልጅም ፡ አባት ፡ ደስ ፡ አይለውም ።
፳፪፤ ደስ ፡ ያላት ፡ ልብ ፡ መልካም ፡ መድኃኒት ፡ ናት ፤
ያዘነች ፡ ነፍስ ፡ ግን ፡ አጥንትን ፡ ታደርቃለች ።

፳፫፤ ኀጥእ ፡ የፍርድን ፡ መንገድ ፡ ለማጥመም ፡
ከብብት ፡ መማለጃን ፡ ይወስዳል ።
፳፬፤ በአስተዋይ ፡ ፊት ፡ ጥበብ ፡ ትኖራለች ፤
የሰነፍ ፡ ዓይን ፡ ግን ፡ በምድር ፡ ዳርቻ ፡ ነው ።
፳፭፤ ሰነፍ ፡ ልጅ ፡ ለአባቱ ፡ ፀፀት ፡ ነው ፥
ለወለደችውም ፡ ምሬት ፡ ነው ።
፳፮፤ ጻድቅን ፡ መቅጣት ፥
ጨዋ ፡ ሰውንም ፡ በጻድቅነቱ ፡ መምታት ፡ መልካም ፡ አይደለም ።
፳፯፤ ጥቂት ፡ ቃልን ፡ የሚናገር ፡ አዋቂ ፡ ነው ፥
መንፈሱም ፡ ቀዝቃዛ ፡ የሆነ ፡ አስተዋይ ፡ ነው ።
፳፰፤ ሰነፍ ፡ ዝም ፡ ቢል ፡ ጠቢብ ፡ ሆኖ ፡ ይቈጠራል ፥
ከንፈሩንም ፡ የሚቈልፍ ፡ — ባለ ፡ አእምሮ ፡ ነው ፡ ይባላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩፤ መለየት ፡ የሚወድድ ፡ ምኞቱን ፡ ይከተላል ፥
መልካሙንም ፡ ጥበብ ፡ ሁሉ ፡ ይቃወማል ።
፪፤ ሰነፍ ፡ የጥበብን ፡ ነገር ፡ አይወድድም ፤
በልቡ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ መግለጥ ፡ ብቻ ፡ ይወድዳል ፡ እንጂ ።
፫፤ ኀጥእ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ንቀት ፡ ደግሞ ፡ ይመጣል ፥
ነውርም ፡ ከስድብ ፡ ጋር ።
፬፤ የሰው ፡ አፍ ፡ ቃል ፡ የጠለቀ ፡ ውኃ ፡ ነው ፥
የጥበብም ፡ ምንጭ ፡ ፈሳሽ ፡ ወንዝ ፡ ነው ።
፭፤ የጻድቅ ፡ ፍርድ ፡ ይጠምም ፡ ዘንድ ፥
ለኀጥእም ፡ ማድላት ፡ መልካም ፡ አይደለም ።
፮፤ የሰነፍ ፡ ከንፈር ፡ በጥል ፡ ውስጥ ፡ ትገባለች ፥
አፉም ፡ በትርን ፡ ትጠራለች ።
፯፤ የሰነፍ ፡ አፍ ፡ ለራሱ ፡ ጥፋት ፡ ነው ፥
ከንፈሩም ፡ ለነፍሱ ፡ ወጥመድ ፡ ነው ።
፰፤ የጆሮ ፡ ጠቢ ፡ ቃል ፡ እንደ ፡ ጣፋጭ ፡ መብል ፡ ነው ፥
እርሱም ፡ እስከ ፡ ሆድ ፡ ጕርጆች ፡ ድረስ ፡ ይወርዳል ።
፱፤ በሥራው ፡ ታካች ፡ የሚሆን ፡
የሀብት ፡ አጥፊ ፡ ወንድም ፡ ነው ።
፲፤ የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የጸና ፡ ግምብ ፡ ነው ፤
ጻድቅ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ሮጦ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
፲፩፤ ለባለጠጋ ፡ ሰው ፡ ሀብቱ ፡ እንደ ፡ ጸናች ፡ ከተማ ፡ ናት ፥
በአሳቡም ፡ እንደ ፡ ረጅም ፡ ቅጥር ።
፲፪፤ ሰው ፡ ሳይወድቅ ፡ በፊት ፡ ልቡ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ፥
ትሕትናም ፡ ክብረትን ፡ ትቀድማለች ።
፲፫፤ ሳይሰማ ፡ ነገርን ፡ በሚመልስ ፡
ስንፍናና ፡ እፍረት ፡ ይሆንበታል ።
፲፬፤ የሰው ፡ ነፍስ ፡ ሕመሙን ፡ ይታገሣል ፤
የተቀጠቀጠን ፡ መንፈስ ፡ ግን ፡ ማን ፡ ያጠነክረዋል ?
፲፭፤ የአስተዋይ ፡ ልብ ፡ እውቀትን ፡ ያገኛል ፥
የጠቢባንም ፡ ጆሮ ፡ እውቀትን ፡ ትፈልጋለች ።
፲፮፤ የሰው ፡ ስጦታ ፡ መንገዱን ፡ ታሰፋለታለች ፥
በታላላቆችም ፡ ፊት ፡ ታገባዋለች ።
፲፯፤ ወደ ፡ ፍርድ ፡ አስቀድሞ ፡ የገባ ፡ ጻድቅ ፡ ይመስላል ፤
ባልንጀራው ፡ ግን ፡ መጥቶ ፡ ይመረምረዋል ።
፲፰፤ ዕጣ ፡ ክርክርን ፡ ትከለክላለች ፥
በኃያላንም ፡ መካከል ፡ ትበይናለች ።
፲፱፤ የተበደለ ፡ ወንድም ፡ እንደ ፡ ጸናች ፡ ከተማ ፡ ጽኑ ፡ ነው ፤
ክርክራቸውም ፡ እንደ ፡ ግንብ ፡ ብረት ፡ ነው ።
፳፤ የሰው ፡ ሆድ ፡ ከአፉ ፡ ፍሬ ፡ ይሞላል ፥
ከንፈሩም ፡ ከሚያፈራው ፡ ይጠግባል ።
፳፩፤ ሞትና ፡ ሕይወት ፡ በምላስ ፡ እጅ ፡ ናቸው ፤
የሚወድዱአትም ፡ ፍሬዋን ፡ ይበላሉ ።
፳፪፤ ሚስት ፡ ያገኘ ፡ በረከትን ፡ አገኘ ፥
ከእግዚአብሔርም ፡ ሞገስን ፡ ይቀበላል ።
፳፫፤ ድሀ ፡ በትሕትና ፡ እየለመነ ፡ ይናገራል ፤
ባለጠጋ ፡ ግን ፡ በድፍረት ፡ ይመልሳል ።
፳፬፤ ብዙ ፡ ወዳጆች ፡ ያሉት ፡ ሰው ፡ ይጠፋል ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ከወንድም ፡ አብልጦ ፡ የሚጠጋጋ ፡ ወዳጅ ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩፤ በከንፈሩ ፡ ከሚወሳልት ፡ ሰነፍ ፡ ይልቅ ፡
ያለ ፡ ነውር ፡ የሚሄድ ፡ ድሀ ፡ ይሻላል ።
፪፤ ነፍስ ፡ እውቀት ፡ የሌለበት ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ መልካም ፡ አይደለም ፤
እግሩንም ፡ የሚያፈጥን ፡ ከመንገድ ፡ ይስታል ።
፫፤ የሰው ፡ ስንፍና ፡ መንገዱን ፡ ታጣምምበታለች ፥
ልቡም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ይቈጣል ።
፬፤ በለጠግነት ፡ ብዙ ፡ ወዳጆች ፡ ይጨምራል ፤
የድሀ ፡ ወዳጅ ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ ይርቃል ።
፭፤ ሐሰተኛ ፡ ምስክር ፡ ሳይቀጣ ፡ አይቀርም ፥
በሐሰትም ፡ የሚናገር ፡ አያመልጥም ።
፮፤ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ለጋሱን ፡ ያቈላምጣሉ ፥
ስጦታ ፡ ለሚሰጥም ፡ ሁሉ ፡ ወዳጅ ፡ ነው ።
፯፤ ድሀን ፡ ሰው ፡ ወንድሞቹ ፡ ሁሉ ፡ ይጠሉታል ፤
ይልቁንም ፡ ወዳጆቹ ፡ ከእርሱ ፡ ይርቃሉ ።
እነርሱንም ፡ በቃል ፡ ቢከተላቸው ፡ አንዳች ፡ አይረቡትም ።
፰፤ ጥበብን ፡ የሚያገኝ ፡ ነፍሱን ፡ ይወድዳል ፥
ማስተዋልንም ፡ የሚጠብቅ ፡ መልካም ፡ ነገርን ፡ ያገኛል ።
፱፤ ሐሰተኛ ፡ ምስክር ፡ ሳይቀጣ ፡ አይቀርም ፤
በሐሰትም ፡ የሚናገር ፡ ይጠፋል ።
፲፤ ለሰነፍ ፡ ቅምጥልነት ፡ አይገባውም ፥
ይልቁንም ፡ በሪያ ፡ በአለቆች ፡ ላይ ፡ ይገዛ ፡ ዘንድ ።
፲፩፤ ሰውን ፡ ጠቢብ ፡ አእምሮው ፡ ከቍጣ ፡ ያዘገየዋል ፥
ለበደለኛውም ፡ ይቅር ፡ ይል ፡ ዘንድ ፡ ክብር ፡ ይሆንለታል ።
፲፪፤ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ግሣት ፡ የንጉሥ ፡ ቍጣ ፡ ነው ፥
ሞገሱም ፡ በመስክ ፡ ላይ ፡ እንዳለ ፡ ጠል ፡ ነው ።
፲፫፤ ሰነፍ ፡ ልጅ ፡ ለአባቱ ፡ ኀዘን ፡ ነው ፥
ጠበኛም ፡ ሚስት ፡ እንደማያቋርጥ ፡ ነጠብጣብ ፡ ናት ።

፲፬ ቤትና ፡ ባለጠግነት ፡ ከአባቶች ፡ ዘንድ ፡ ይወረሳሉ ፤
አስተዋይ ፡ ሚስት ፡ ግን ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ዘንድ ፡ ናት ።

፲፭ ተግባር ፡ መፍታት ፡ እንቅልፍን ፡ ታመጣለች ÷
የታካችም ፡ ነፍስ ፡ ትራባለች ።

፲፮ ትእዛዝን ፡ የሚጠብቅ ፡ ነፍሱን ፡ ይጠብቃል ፤
መንገዱን ፡ ቸል ፡ የሚል ፡ ግን ፡ ይጠፋል ።

፲፯ ለድሀ ፡ ቸርነትን ፡ የሚያደርግ ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ ያበድራል ÷
በጎነቱንም ፡ መልሶ ፡ ይከፍለዋል ።

፲፰ ተስፋ ፡ ገና ፡ ሳለች ፡ ልጅህን ፡ ገሥጽ ÷
መሞቱንም ፡ አትሻ ።

፲፱ ንዴተኛ ፡ ሰው ፡ መቀጮ ፡ ይከፍላል ፤
ብታድነውም ፡ ደግሞ ፡ ትጨምራለህ ።

፳ ምክርን ፡ ስማ ÷ ተግሣጽንም ፡ ተቀበል ፡
በፍጻሜህ ፡ ጠቢብ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ።

፳፩ በሰው ፡ ልብ ፡ ብዙ ፡ አሳብ ፡ አለ ፤
የእግዚአብሔር ፡ ምክር ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ ይጸናል ።

፳፪ የሰው ፡ ቸርነት ፡ የእርሱ ፡ ፍሬ ፡ ነው ፤
ከሐሰተኛ ፡ ባለጠጋም ፡ እውነተኛ ፡ ድሀ ፡ ይሻ
ላል ።

፳፫ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ወደ ፡ ሕይወት ፡
ይመራል ፤
የሚፈራውም ፡ ጠግቦ ፡ ይኖራል ÷
ክፉ ፡ ነገርም ፡ አያገኘውም ።

፳፬ ታካች ፡ ሰው ፡ እጁን ፡ በወጭቱ ፡ ያጠልቃታል ÷
ወደ ፡ አፉ ፡ ስንኳ ፡ አይመልሳትም ።

፳፭ ፌዘኛን ፡ ብትገርፈው ፡ አላዋቂ ፡ ብልሃተኛ ፡
ይሆናል ፤
አስተዋይን ፡ ሰው ፡ ብትገሥጸው ፡ እውቀትን ፡
ያገኛል ።

፳፮ አባቱን ፡ የሚያስከፋ ፡ እናቱንም ፡ የሚያሳድድ ፡
የሚያሳፍርና ፡ ጐስቋላ ፡ ልጅ ፡ ነው ።

፳፯ ልጄ ፡ ሆይ ÷ ተግሣጽን ፡ ከሰማህ ፡ በኋላ ፡
ከእውቀት ፡ ቃል ፡ መሳሳትን ፡ ተው ።

፳፰ ወስላታ ፡ ምስክር ፡ በፍርድ ፡ ያፌዛል ÷
የኀጥአንም ፡ አፍ ፡ ክፋትን ፡ ይውጣል ።

፳፱ ለሚያፌዙ ፡ ሰዎች ፡ ፍርድ ፡ ተዘጋጅታለች ÷
ለሰነፎችም ፡ ጀርባ ፡ በትር ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ፌዘኛ ፡ ያደርጋል ÷ ብርቱ ፡ መጠ
ጥም ፡ ጠበኛ ፡ ያደርጋል ፤
በዚህም ፡ የሳተ ፡ ሁሉ ፡ ጠቢብ ፡ አይደለም ።

፪ የንጉሥ ፡ ቍጣ ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ግሣት ፡ ነው ፤
የሚያስቈጣውም ፡ ሰው ፡ የራሱን ፡ ነፍስ ፡ ይበ
ድላል ።

፫ ከክርክር ፡ ይርቅ ፡ ዘንድ ፡ ለሰው ፡ ክብሩ ፡ ነው ፤
ሰነፍ ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ ባለ ፡ ነገር ፡ ይጣ
መራል ።

፬ ታካች ፡ ሰው ፡ በብርድ ፡ ምክንያት ፡ አያርስም ፤
ስለዚህ ፡ በመከር ፡ ይለምናል ÷ ምንም ፡ አያገ
ኝም ።

፭ ምክር ፡ በሰው ፡ ልብ ፡ እንደ ፡ ጠሊቅ ፡ ውኃ ፡ ነው ፤
አእምሮ ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ይቀዳዋል ።

፮ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ቸርነታቸውን ፡ ያወራሉ ፤
የታመነውን ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ማን ፡ ያገኘዋል ?

፯ ጻድቅ ፡ ያለ ፡ ነውር ፡ ይሄዳል ÷
ልጆቹም ፡ ከእርሱ ፡ በኋላ ፡ ምስጉኖች ፡ ናቸው ።

፰ በፍርድ ፡ ወንበር ፡ የተቀመጠ ፡ ንጉሥ ፡
ክፉውን ፡ ሁሉ ፡ በዓይኖቹ ፡ ይበትናል ።

፱ ልቤን ፡ አነጻሁ ÷
ከኃጢአትም ፡ ጠራሁ ፡ የሚል ፡ ማን ፡ ነው ?

፲ ሁለት ፡ ዓይነት ፡ ሚዛንና ፡ ሁለት ፡ ዓይነት ፡ መስ
ፈሪያ ÷
ሁለቱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ርኩሳን ፡ ናቸው ።

፲፩ ሕፃን ፡ ቅንና ፡ ንጹሕ ፡ መሆኑ ፡
በሚያደርገው ፡ ሥራ ፡ ይታወቃል ።

፲፪ የሚሰማ ፡ ጆሮንና ፡ የሚያይ ፡ ዓይንን ÷
ሁለቱን ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈጠራቸው ።

፲፫ ድሀ ፡ እንዳትሆን ፡ እንቅልፍን ፡ አትውደድ ፤
ዓይንህን ፡ ክፈት ÷ እንጀራም ፡ ትጠግባለህ ።

፲፬ የሚገዛ ፡ ሰው ፡— ክፉ ፡ ነው ፡ ክፉ ፡ ነው ፡ ይላል ፤
በሄደ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ይመካል ።

፲፭ ወርቅና ፡ ብዙ ፡ ቀይ ፡ ዕንቍ ፡ ይገኛል ፤
የእውቀት ፡ ከንፈር ፡ ግን ፡ የከበረች ፡ ጌጥ ፡ ናት ።

፲፮ ለማያውቀው ፡ ከተዋሰ ፡ ሰው ፡ ልብሱን ፡ ውሰድ ÷
ለእንግዳ ፡ የተዋሰውንም ፡ እርሱን ፡ አግተው ።

፲፯ የሐሰት ፡ እንጀራ ፡ ለሰው ፡ የጣፈጠ ፡ ነው ፤
ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ አፉ ፡ ጭንጫ ፡ ይሞላል ።

፲፰ አሳብ ፡ በምክር ፡ ትጸናለች ÷
በመልካምም ፡ ምክር ፡ ሰልፍ ፡ አድርግ ።

፲፱ ዘዋሪ ፡ ሐሜተኛ ፡ ምሥጢርን ፡ ይገልጣል ፤
ከንፈሩን ፡ የሚያሞጠሙጥ ፡ ሰውን ፡ አትገና
ኘው ።

፳ አባቱን ፡ ወይም ፡ እናቱን ፡ የሚሰድብ ÷
በድቅድቅ ፡ ጨለማ ፡ መብራቱ ፡ ይጠፋል ።

፳፩ በመጀመሪያ ፡ ፈጥኖ ፡ የተከማቸ ፡ ርስት ፡
ፍጻሜው ፡ አይባረክም ።

፳፪ ክፉ ፡ እመልሳለሁ ፡ አትበል ፤
እግዚአብሔርን ፡ ተማመን ÷ እርሱም ፡ ያድ
ንሃል ።

፳፫ ሁለት ፡ ዓይነት ፡ ሚዛን ፡ በእግዚአብሔር ፡
ዘንድ ፡ አስጸያፊ ፡ ነው ÷
ሐሰተኛ ፡ ሚዛንም ፡ መልካም ፡ አይደለም ።

፳፬ የሰው ፡ አካሄዱ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤
እንግዲያስ ፡ ሰው ፡ መንገዱን ፡ እንዴት ፡ ያስተ
ውላል ?

፳፭ ሰው ፡ በችኰላ ፡— ለእግዚአብሔር ፡ የተቀ
ደሰ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ቢሳል ÷
ከተሳለም ፡ በኋላ ፡ ቢፀፀት ፡ ወጥመድ ፡ ነው ።

፳፮ ጠቢብ ፡ ንጉሥ ፡ ኀጥአንን ፡ በመንሽ ፡ ይበ
ትናቸዋል ÷
መንኰራኵሩንም ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ያንኰራኵ
ርባቸዋል ።

፳፯ የሰው ፡ መንፈስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መብራት ፡
ነው ፡
የሆዱን ፡ ጕርጆች ፡ ሁሉ ፡ የሚመረምር ።

፳፰ ቸርነትና ፡ እውነት ፡ ንጉሥን ፡ ይጠብቁታል ፤
ዙፋኑም ፡ በቸርነት ፡ ይበረታል ።
፳፱ የጎበዛዝት ፡ ክብር ፡ ጕልበታቸው ፡ ናት ፥
የሽማግሌዎችም ፡ ጌጥ ፡ ሽበት ፡ ነው ።
፴ የሰንበር ፡ ቍስል ፡ ክፉዎችን ፡ ያነጻል ፤
ግርፋትም ፡ ወደ ፡ ሆድ ፡ ጕርጆች ፡ ይገባል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ የንጉሥ ፡ ልብ ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ ፈሳሾች ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ነው ፤
ወደ ፡ ወደደውም ፡ ያዘነብለዋል ።
፪ የሰው ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ በዓይኑ ፡ ፊት ፡ የቀናች ፡ ትመስለዋለች ፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ልብን ፡ ይመዝናል ።
፫ እግዚአብሔር ፡ ከመሥዋዕት ፡ ይልቅ ፡
ጽድቅንና ፡ ቅን ፡ ነገርን ፡ ማድረግ ፡ ይወድዳል ።
፬ ትዕቢተኛ ፡ ዓይንና ፡ ደፋር ፡ ልብ ፡ የኀጥአንም ፡
እርሻ ፡ ኃጢአት ፡ ነው ።
፭ የትጉህ ፡ አሳብ ፡ ወደ ፡ ጥጋብ ፡ ያደርሳል ፤
ችኵል ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ለመጕደል ፡ ይቸኩላል ።
፮ በሐሰተኛ ፡ ምላስ ፡ መዝገብ ፡ ማከማቸት ፡ የሚበንን ፡ ጕም ፡ ነው ፤
ይህን ፡ የሚፈልጉ ፡ ሞትን ፡ ይፈልጋሉ ።
፯ ቅን ፡ ነገርን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አይወድዱምና ፡
የኀጥአን ፡ ንጥቂያ ፡ ራሳቸውን ፡ ያጠፋቸዋል ።
፰ የበደለኛ ፡ መንገድ ፡ የጠመመች ፡ ናት ፤
የንጹሕ ፡ ሥራ ፡ ግን ፡ የቀና ፡ ነው ።
፱ ከጠበኛ ፡ ሴት ፡ ጋር ፡ በአንድ ፡ ቤት ፡ ከመቀመጥ ፡
በውጪ ፡ በቤት ፡ ማዕዘን ፡ ላይ ፡ መቀመጥ ፡ ይሻላል ።
፲ የኀጥእ ፡ ነፍስ ፡ ክፉን ፡ ትመኛለች ፥
በፊቱም ፡ ባልንጀራው ፡ ሞገስን ፡ አያገኝም ።
፲፩ ፌዘኛ ፡ ቅጣትን ፡ በተቀበለ ፡ ጊዜ ፡ አላዋቂ ፡ ሰው ፡ ጥበብን ፡ ያገኛል ፤
ጠቢብም ፡ ቢማር ፡ እውቀትን ፡ ይቀበላል ።
፲፪ ጻድቅ ፡ ስለ ፡ ኀጥእ ፡ ቤት ፡ ያስባል ፥
ኀጥአንም ፡ ለጥፋት ፡ እንደ ፡ ተገለበጡ ።
፲፫ የድሀውን ፡ ጩኸት ፡ እንዳይሰማ ፡ ጆሮውን ፡ የሚደፍን ፡ ሰው ፥
እርሱ ፡ ራሱ ፡ ይጮኻል ፡ አይሰማለትምም ።
፲፬ ስጦታ ፡ በስውር ፡ ቍጣን ፡ ታጠፋለች ፥
የብብትም ፡ ውስጥ ፡ ጉቦ ፡ ጽኑ ፡ ቍጣን ፡ ታበርዳለች ።
፲፭ ፍርድን ፡ ማድረግ ፡ ለጻድቅ ፡ ደስታ ፡ ነው ፤
ኃጢአትን ፡ ለሚያደርጉ ፡ ግን ፡ ጥፋት ፡ ነው ።
፲፮ ከማስተዋል ፡ መንገድ ፡ የሚሳሳት ፡ ሰው ፡
በሙታን ፡ ጉባኤ ፡ ያርፋል ።
፲፯ ተድላ ፡ የሚወድድ ፡ ድሀ ፡ ይሆናል ፥
የወይን ፡ ጠጅንና ፡ ዘይትንም ፡ የሚወድድ ፡ ባለጠጋ ፡ አይሆንም ።
፲፰ ኀጥእ ፡ የጻድቅ ፡ ቤዛ ፡ ነው ፤
በደለኛም ፡ የቅን ፡ ሰው ፡ ቤዛ ፡ ነው ።
፲፱ ከጠበኛና ፡ ከቍጡ ፡ ሴት ፡ ጋር ፡ ከመቀመጥ ፡
በምድረ ፡ በዳ ፡ መቀመጥ ፡ ይሻላል ።
፳ የከበረ ፡ መዝገብና ፡ ዘይት ፡ በጠቢብ ፡ ሰው ፡ ቤት ፡ ይኖራል ፤
አእምሮ ፡ የሌለው ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ይውጠዋል ።
፳፩ ጽድቅንና ፡ ምሕረትን ፡ የሚከተል ፡
ሕይወትንና ፡ ጽድቅን ፡ ክብርንም ፡ ያገኛል ።
፳፪ ጠቢብ ፡ የኃያላንን ፡ ከተማ ፡ ይገባበታል ፥
የሚታመኑበትንም ፡ ኃይል ፡ ያፈርሳል ።
፳፫ አፉንና ፡ ምላሱን ፡ የሚጠብቅ ፡
ነፍሱን ፡ ከመከራ ፡ ይጠብቃል ።
፳፬ ኵሩና ፡ ተጓዳጅ ፡ ሰው ፡ ፌዘኛ ፡ ይባላል ፤
እርሱም ፡ በትዕቢት ፡ ቍጣ ፡ ያደርጋል ።
፳፭ ታካችን ፡ ምኞቱ ፡ ትገድለዋለች ፥
እጆቹ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ አይፈቅዱምና ።
፳፮ ኀጥእ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ምኞትን ፡ ይመኛል ፤
ጻድቅ ፡ ግን ፡ ይሰጣል ፥ አይሰስትም ።
፳፯ የኀጥአን ፡ መሥዋዕት ፡ አስጸያፊ ፡ ነው ፤
ይልቁንም ፡ በክፉ ፡ አሳብ ፡ ሲያቀርቡት ፡ አስጸያፊ ፡ ነው ።
፳፰ ሐሰተኛ ፡ ምስክር ፡ ይጠፋል ፤
የሚሰማ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ተጠንቅቆ ፡ ይናገራል ።
፳፱ ኀጥእ ፡ ፊቱን ፡ ያጠነክራል ፤
ቅን ፡ ሰው ፡ ግን ፡ መንገዱን ፡ ያጸናል ።
፴ ጥበብ ፡ ወይም ፡ ማስተዋል ፡ ወይም ፡ ምክር ፡
በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ የለም ።
፴፩ ፈረስ ፡ ለጦርነት ፡ ቀን ፡ ይዘጋጃል ፤
ድል ፡ ግን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ መልካም ፡ ስም ፡ ከብዙ ፡ ባለጠግነት ፡ ይሻላል ፥
መልካምም ፡ ሞገስ ፡ ከብርና ፡ ከወርቅ ፡ ይበልጣል ።
፪ ባለጠጋና ፡ ድሀ ፡ ተገናኙ ፤
እግዚአብሔር ፡ የሁላቸው ፡ ፈጣሪ ፡ ነው ።
፫ ብልህ ፡ ሰው ፡ ክፉን ፡ አይቶ ፡ ይሸሸጋል ፤
አላዋቂዎች ፡ ግን ፡ አልፈው ፡ ይጐዳሉ ።
፬ ትሕትናና ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡
ባለጠግነት ፡ ክብር ፡ ሕይወትም ፡ ነው ።
፭ እሾህና ፡ ወጥመድ ፡ በጠማማ ፡ ሰው ፡ መንገድ ፡ ናቸው ፤
ነፍሱን ፡ ግን ፡ የሚጠብቅ ፡ ከእነርሱ ፡ ይርቃል ።
፮ ልጅን ፡ በሚሄድበት ፡ መንገድ ፡ ምራው ፥
በሸመገለም ፡ ጊዜ ፡ ከእርሱ ፡ ፈቀቅ ፡ አይልም ።
፯ ባለጠጋ ፡ ድሆችን ፡ ይገዛል ፥
ተበዳሪም ፡ የአበዳሪ ፡ ባሪያ ፡ ነው ።
፰ ኃጢአትን ፡ የሚዘራ ፡ መከራን ፡ ያጭዳል ፥
የቍጣውም ፡ በትር ፡ ይጠፋል ።
፱ ርኅሩህ ፡ የተባረከ ፡ ይሆናል ፥
ከእንጀራው ፡ ለድሀ ፡ ሰጥቶአልና ።
፲ ፌዘኛን ፡ ብታወጣ ፡ ክርክር ፡ ይወጣል ፥
ጠብና ፡ ስድብም ፡ ያልቃል ።
፲፩ የልብን ፡ ንጽሕና ፡ የሚወድድና ፡ ሞገስ ፡ በከንፈሩ ፡ ያለች ፥

ንጉሥ ፡ ወዳጁ ፡ ይሆናል ።
፲፪፤ የእግዚአብሔር ፡ ዓይኖች ፡ እውቀትን ፡ ይጠብቃሉ ፤
እርሱ ፡ ግን ፡ የወስላታውን ፡ ቃል ፡ ይገለብጣል ።
፲፫፤ ታካች ፡ ሰው ፡— አንበሳ ፡ በሜዳ ፡ ነው ፤
በመንገዱ ፡ ላይ ፡ እሞታለሁ ፡ ይላል ።
፲፬፤ የጋለሞታ ፡ ሴት ፡ አፍ ፡ የጠለቀ ፡ ጕድጓድ ፡ ነው ፤
እግዚአብሔር ፡ የተቈጣው ፡ በእርስዋ ፡ ይወድቃል ።
፲፭፤ ስንፍና ፡ በሕፃን ፡ ልብ ፡ ታስሮአል ፤
የተግሣጽ ፡ በትር ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ ያርቃታል ።
፲፮፤ ለራሱ ፡ ጥቅም ፡ ለመጨመር ፡ ሲል ፡ ድሀን ፡ የሚጐዳ ÷
ለባለጠጋም ፡ የሚሰጥ ÷ እርሱ ፡ ወደ ፡ ድህነት ፡ ይወድቃል ።

፲፯፤ ጆሮህን ፡ አዘንብለህ ፡ የጠቢባንን ፡ ቃላት ፡ ስማ ÷
ልብህንም ፡ ወደ ፡ እውቀቴ ፡ አድርግ ፤
፲፰፤ እነርሱን ፡ በውስጥህ ፡ ብትጠብቅ ÷
በከንፈሮችህም ፡ ላይ ፡ የተዘጋጁ ፡ ቢሆኑ ÷ የተወደደ ፡ ነገር ፡ ይሆንልሃልና ።
፲፱፤ እምነትህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡
ለአንተ ፡ ዛሬ ፡ እነሆ ፡ አስታወቅሁህ ።
፳፤ ፳፩፤ የእውነትን ፡ ቃል ፡ እርግጥነት ፡ አስታውቅህ ፡ ዘንድ ÷
ለሚጠይቅህም ፡ እውነትን ፡ ቃል ፡ መመለስ ፡ ይቻልህ ፡ ዘንድ ÷
በምክርና ፡ በእውቀት ፡ የከበረን ፡ ነገር ፡ አልጻፍሁልህምን ?

፳፪፤ ድሀን ፡ በግድ ፡ አትበለው ፡ ድሀ ፡ ነውና ፤
ችግረኛውንም ፡ በበር ፡ አትግፋው ፤
፳፫፤ እግዚአብሔር ፡ የእነርሱን ፡ ፍርድ ፡ ይፋረድላቸዋልና ÷
የቀሙአቸውንም ፡ ሰዎች ፡ ሕይወት ፡ ይቀማልና ።
፳፬፤ ከቍጡ ፡ ሰው ፡ ጋር ፡ ባልንጀራ ፡ አትሁን ÷
ከወፈፍተኛም ፡ ጋር ፡ አትሂድ ÷
፳፭፤ መንገዱን ፡ እንዳትማር ፡
ለነፍስህም ፡ ወጥመድ ፡ እንዳታገኝህ ።
፳፮፤ እጃቸውን ፡ አጋና ፡ እንደሚማቱ ÷
ለባለ ፡ ዕዳዎች ፡ እንደሚዋሱ ፡ አትሁን ፤
፳፯፤ የምትከፍለው ፡ ባይኖርህ ÷
ምንጣፍህን ፡ ከበታችህ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይወስዳል ?
፳፰፤ አባቶችህ ፡ የሠሩትን ፡ የቀድሞውን ፡ የድንበር ፡ ምልክት ፡ አታፍልስ ።
፳፱፤ በሥራው ፡ የቀጠፈ ፡ ሰውን ፡ አይተሃልን ?
በነገሥታት ፡ ፊት ፡ ይቆማል ፤
በተዋረዱም ፡ ሰዎች ፡ ፊት ፡ አይቆምም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩፤ ከመኰንን ፡ ጋር ፡ ለመብላት ፡ በተቀመጥህ ፡ ጊዜ ÷
በፊትህ ፡ ያለውን ፡ በደኅና ፡ አስተውል ፤
፪፤ ሰውነትህም ፡ ቢሳሳ ÷
በጕሮሮህ ፡ ላይ ፡ ካራ ፡ አድርግ ።
፫፤ ጣፋጩ ፡ መብል ፡ አይመርህ ፡
የሐሰት ፡ እንጀራ ፡ ነውና ።
፬፤ ባለጠጋ ፡ ለመሆን ፡ አትድከም ፤
የገዛ ፡ ራስህን ፡ ማስተዋል ፡ ተው ።
፭፤ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ዓይንህን ፡ ብታዘወትርበት ፡ ይጠፋል ፤
በለጠግነት ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ እንደሚበርር ፡ እንደ ፡ ንስር ፡
ለራሱ ፡ ክንፍ ፡ ያበጃልና ።
፮፤ የቀናተኛን ፡ ሰው ፡ እንጀራ ፡ አትብላ ÷
ጣፋጩ ፡ መብልም ፡ አይመርህ ፤
፯፤ በልቡ ፡ እንዳሰበ ፡ እንዲሁ ፡ ነውና ፤
ብላ ፡ ጠጣ ፡ ይልሃል ÷ ልቡ ፡ ግን ፡ ከንተ ፡ ጋር ፡ አይደለም ።
፰፤ የበላኸውን ፡ መብል ፡ ትተፋዋለህ ÷
ያማረውንም ፡ ቃልህን ፡ ታጠፋዋለህ ።
፱፤ በሰነፍ ፡ ጆሮ ፡ አንዳች ፡ አትናገር ÷
የቃልህን ፡ ጥበብ ፡ ያፌዝብሃልና ።
፲፤ የቀድሞውን ፡ የድንበር ፡ ምልክት ፡ አታፍልስ ፤
ወደ ፡ ድሀ ፡ አደጎች ፡ እርሻ ፡ አትግባ ፤
፲፩፤ ታዳጊአቸው ፡ ጽኑ ፡ ነውና ÷
እርሱም ፡ ፍርዳቸውን ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይፋረዳልና ።
፲፪፤ ልብህን ፡ ለተግሣጽ ፡ ስጥ ÷
ጆሮህንም ፡ ወደ ፡ እውቀት ፡ ቃል ።
፲፫፤ ሕፃንን ፡ ከመቅጣት ፡ ቸል ፡ አትበል ÷
በበትር ፡ ብትመታው ፡ አይሞትምና ።
፲፬፤ በበትር ፡ ትመታዋለህ ÷
ነፍሱንም ፡ ትታደጋለህ ።
፲፭፤ ልጄ ፡ ሆይ ÷ ልብህ ፡ ጠቢብ ፡ ቢሆን ፡
ልቤ ፡ ደግሞ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤
፲፮፤ ከንፈሮችህም ፡ በቅን ፡ ቢናገሩ ፡
ኵላሊቶቼ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፲፯፤ ልብህ ፡ በኃጢአተኞች ፡ አይቅና ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ቀኑን ፡ ሙሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በመፍራት ፡ ኑር ፤
፲፰፤ በእውነት ፡ ፍጻሜ ፡ አለህና ÷
ተስፋህም ፡ አይጠፋምና ።

፲፱፤ ልጄ ፡ ሆይ ÷ ስማ ፡ ጠቢብም ፡ ሁን ÷
ልብህንም ፡ በቀናው ፡ መንገድ ፡ ምራ ።
፳፤ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ከሚጠጡ ፡ ጋር ፡ አትቀመጥ ፡
ለሥጋም ፡ ከሚሣሡ ፡ ጋር ፤
፳፩፤ ሰካርና ፡ ሆዳም ፡ ይደኸያሉና ÷
የእንቅልፍም ፡ ብዛት ፡ የተበጫጨቀ ፡ ጨርቅ ፡ ያስለብሳልና ።

፳፪፤ የወለደህን ፡ አባትህን ፡ ስማ ÷
እናትህም ፡ ባረጀች ፡ ጊዜ ፡ አትናቃት ።
፳፫፤ እውነትን ፡ ግዛ ፡ አትሽጣትም ÷
ጥበብን ፡ ተግሣጽን ፡ ማስተዋልንም ።
፳፬፤ የጻድቅ ፡ አባት ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ÷

ጠቢብንም ፡ ልጅ ፡ የወለደ ፡ ሐሤትን ፡ ያገኛል ።
፳፭ ፡ አባትህና ፡ እናትህ ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፥
አንተንም ፡ የወለደች ፡ ደስ ፡ ይበላት ።

፳፮ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ልብህን ፡ ስጠኝ ፥
ዓይኖችህም ፡ መንገዴን ፡ ይውደዱ ።
፳፯ ፡ ጋለሞታ ፡ ሴት ፡ የጠለቀች ፡ ዐዘቅት ፡ ናትና ፥
ሌላይቱም ፡ ሴት ፡ የጠበበች ፡ ጉድጓድ ፡ ናትና ።
፳፰ ፡ እንደ ፡ ሌባ ፡ ታደባለች ፥
ወስላቶችንም ፡ በሰው ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ታበዛለች ።

፳፱ ፡ ዋይታ ፡ ለማን ፡ ነው ? ኀዘን ፡ ለማን ፡ ነው ? ጠብ ፡ ለማን ፡ ነው ? ጩኸት ፡ ለማን ፡ ነው ?
ያለ ፡ ምክንያት ፡ መቍሰል ፡ ለማን ፡ ነው ? የዓይን ፡ ቀላት ፡ ለማን ፡ ነው ?
፴ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ በመጠጣት ፡ ለሚዘገዩ ፡ አይደለምን ?
የተደባለቀ ፡ የወይንን ፡ ጠጅ ፡ ይፈትኑ ፡ ዘንድ ፡ ለሚከተሉ ፡ አይደለምን ?
፴፩ ፡ ወደ ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡ አትመልከት ፡
በቀላ ፡ ጊዜ ፥ መልኩም ፡ በብርሌ ፡ በንጸባረቀ ፡ ጊዜ ፥
እየጣፈጠም ፡ በገባ ፡ ጊዜ ።
፴፪ ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ እባብ ፡ ይነድፋል ፥
እንደ ፡ እፉኝትም ፡ መርዙን ፡ ያፈስሳል ።
፴፫ ፡ ዓይኖችህ ፡ ጋለሞታዎችን ፡ ያያሉ ፥
ልብህም ፡ ጠማማ ፡ ነገርን ፡ ይናገራል ።
፴፬ ፡ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ ተኛ ፡ ትሆናለህ ፥
በደቀልም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተኛ ።
፴፭ ፡ መቱኝ ፥ ያውም ፡ አልተሰማኝም ፤
ጐሰሙኝ ፥ አላወቅሁምም ።
መቼ ፡ እነቃለሁ ?
ደግሞ ፡ ጨምሬ ፡ እሻታለሁ ፡ ትላለህ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ በክፉ ፡ ሰዎች ፡ አትቅና ፥
ከእነርሱ ፡ ጋርም ፡ መሆንን ፡ አትውደድ ፤
፪ ፡ ልባቸው ፡ ግፍን ፡ ታስባለችና ፥
ከንፈራቸውም ፡ ሽንገላን ፡ ትናገራለችና ።
፫ ፡ ቤት ፡ በጥበብ ፡ ይሠራል ፥
በማስተዋልም ፡ ይጸናል ፤
፬ ፡ በእውቀት ፡ ከከበረውና ፡ ካማረው ፡ ሀብት ፡ ሁሉ ፡
ጓዳዎች ፡ ይሞላሉ ።
፭ ፡ ጠቢብ ፡ ሰው ፡ ብርቱ ፡ ነው ፥
አዋቂም ፡ ሰው ፡ ኃይሉን ፡ ያበዛል ።
፮ ፡ በመልካም ፡ ሥርዓት ፡ ሰልፍ ፡ ታደርጋለህ ፤
ድልም ፡ ብዙ ፡ ምክር ፡ ባለበት ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
፯ ፡ ጥበብ ፡ ለሰነፍ ፡ ከፍ ፡ ብላ ፡ የራቀች ፡ ናት ፤
በበርም ፡ አፉን ፡ አይከፍትም ።

፰ ፡ ክፉ ፡ ለማድረግ ፡ የሚያስብ ፡
ተንኰለኛ ፡ ይባላል ።
፱ ፡ የስንፍና ፡ ሐሳብ ፡ ኃጢአት ፡ ነው ፤
ሰዎች ፡ ፌዘኛውን ፡ ይጸየፉታል ።

፲ ፡ በመከራ ፡ ቀን ፡ ብትላላ ፡
ጉልበትህ ፡ ጥቂት ፡ ነው ።
፲፩ ፡ ወደ ፡ ሞት ፡ የሚነዱትን ፡ ታደግ ፤
ሊታረዱ ፡ የተወሰኑትን ፡ አድን ።
፲፪ ፡ እነሆ ፥ ይህን ፡ አላውቀውም ፡ ብትል ፥
ልቦችን ፡ የሚመረምር ፡ እርሱ ፡ አያስተውልምን ?
ነፍስህንም ፡ የሚመለከት ፡ እርሱ ፡ አያውቅምን ?
ለሰውስ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሥራው ፡ አይመልስለትምን ?

፲፫ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ መልካም ፡ ነውና ፡ ማር ፡ ብላ ፤
ወለላም ፡ ለጣምህ ፡ ጣፋጭ ፡ ነው ።
፲፬ ፡ ጥበብም ፡ ለነፍስህ ፡ እንዲሁ ፡ እንደሚሆን ፡ እወቅ ፤
ብታገኘውም ፡ ፍጻሜህ ፡ መልካም ፡ ይሆናል ፥
ተስፋህም ፡ አይጠፋም ።

፲፭ ፡ እንደ ፡ ኀጥእ ፡ በጻድቅ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ አትሸምቅ ፤
ማደሪያውንም ፡ አታውክ ።
፲፮ ፡ ጻድቅ ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ ይወድቃልና ፥ ይነሣማል ፤
ኀጥአን ፡ ግን ፡ በክፉ ፡ ላይ ፡ ይወድቃሉ ።

፲፯ ፡ ጠላትህ ፡ ቢወድቅ ፡ ደስ ፡ አይበልህ ፥
በመሰናከሉም ፡ ልብህ ፡ ሐሤት ፡ አያድርግ ፥
፲፰ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያንን ፡ አይቶ ፡ በዓይኑ ፡ ክፉ ፡ እንዳይሆን ፥
ቍጣውንም ፡ ከእርሱ ፡ እንዳይመልስ ።

፲፱ ፡ ስለ ፡ ኃጢአተኞች ፡ አትቈጣ ፥
በክፉዎችም ፡ አትቅና ።
፳ ፡ ለኃጢአተኛ ፡ የፍጻሜ ፡ ተስፋ ፡ የለውምና ፥
የኀጥአንም ፡ መብራት ፡ ይጠፋልና ።

፳፩ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔርንና ፡ ንጉሥን ፡ ፍራ ፥
ከዓመፀኞችም ፡ ጋር ፡ አትደባለቅ ።
፳፪ ፡ መከራቸው ፡ ድንገት ፡ ይነሣልና ፤
ከሁለቱ ፡ የሚመጣውን ፡ ጥፋት ፡ ማን ፡ ያውቃል ?

(የሚቀጥለው ፡ ከግሪክ ፡ የተጨመረ ፡ ነው ።)

የነገሩትን ፡ የሚሰማ ፡ ልጅ ፡ ከጥፋት ፡ የራቀ ፡ ነው ፤
የነገሩትን ፡ የሚቀበልን ፡ ሰው ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቀበለዋል ።
ከንጉሥ ፡ አንደበት ፡ ምንምን ፡ ሐሰት ፡ ይነገራል ፡ አይባልም ፤
ከአንደበቱም ፡ የሚወጣ ፡ ሐሰት ፡ የለም ።
የንጉሥ ፡ ቃል ፡ ሾተል ፡ ናት ፤
ለጥፋት ፡ የተሰጠችውን ፡ ሰው ፡ ሰውነት ፡ ታጠፋዋለች ፡ እንጂ ፡ አንድ ፡ አካል ፡ ብቻ ፡ የምታጠፋ ፡ አይደለም ።

ሰይፈ ፡ መዓቱ ፡ ብትሳል ፡ ግን ፡
ከወገኑ ፡ ጋር ፡ ሰውን ፡ ታጠፋለች ፤
ከአሞሮች ፡ ግልገል ፡ ወገን ፡ የማይበላ ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡
እንደ ፡ እሳት ፡ ነበልባል ፡ ታቃጥላለች ።

፳፫ እነዚህ ፡ ደግሞ ፡ የጠቢባን ፡ ቃሎች ፡ ናቸው ።
በፍርድ ፡ ታደላ ፡ ዘንድ ፡ መልካም ፡ አይደለም ።
፳፬ ኃጥኡን ፡— ጻድቅ ፡ ነህ ፡ የሚለውን ፡
ወገኖች ፡ ይረግሙታል ፡ አሕዛብም ፡ ይጠሉታል ፤
፳፭ የሚዘልፉት ፡ ግን ፡ ደስታ ፡ ይሆንላቸዋል ፥
በላያቸውም ፡ መልካም ፡ በረከት ፡ ትመጣላቸዋለች ።
፳፮ በቀና ፡ ነገር ፡ የሚመልስ ፡ ከንፈርን ፡ ይስማል ።
፳፯ በስተ ፡ ሜዳ ፡ ሥራህን ፡ አሰናዳ ፥
ስለ ፡ አንተ ፡ በእርሻ ፡ አዘጋጅት ፤
ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ቤትህን ፡ ሥራ ።
፳፰ በባልንጀራህ ፡ ላይ ፡ በከንቱ ፡ ምስክር ፡ አትሁን ፥
በከንፈርህም ፡ አታብለው ።
፳፱ እንዳደረገብኝ ፡ እንዲሁ ፡ አደርግበታለሁ ፥
እንደ ፡ ሥራውም ፡ እመልስበታለሁ ፡ አትበል ።
፴ በታካች ፡ ሰው ፡ እርሻ ፥
አእምሮ ፡ በጐደለውም ፡ ሰው ፡ ወይን ፡ በታ ፡ አለፍሁ ።
፴፩ እነሆም ፥ ሁሉ ፡ እሾህ ፡ ሞልቶበታል ፥
ፊቱንም ፡ ሳማ ፡ ሸፍኖታል ፥
የድንጋዩም ፡ ቅጥር ፡ ፈርሶአል ።
፴፪ ተመለከትሁና ፡ አሰብሁ ፤
አየሁትና ፡ ተግሣጽን ፡ ተቀበልሁ ።
፴፫ ጥቂት ፡ ትተኛለህ ፥ ጥቂትም ፡ ታንቀላፋለህ ፥
ትተኛም ፡ ዘንድ ፡ ጥቂት ፡ እጅህን ፡ ታጥፋለህ ፤
፴፬ እንግዲህ ፡ ድህነትህ ፡ እንደ ፡ ወንበዴ ፥
ችጋርህም ፡ ሰይፍ ፡ እንደ ፡ ታጠቀ ፡ ሰው ፡ ይመጣብሃል ።

(በግዕዝ ፡ መጽሐፈ ፡ ተግሣጽ ፡ ይባላል ፡)

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ። (፩)

፩ እነዚህም ፡ ደግሞ ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ የሕዝቅያስ ፡ ሰዎች ፡ የቀዱአቸው ፡ የሰሎሞን ፡ ምሳሌዎች ፡ ናቸው ።
፪ የእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ ነገርን ፡ መሰወር ፡ ነው ፤
የነገሥታት ፡ ክብር ፡ ግን ፡ ነገርን ፡ መመርመር ፡ ነው ።
፫ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከፍታ ፡ እንደ ፡ ምድርም ፡ ጥልቀት ፡
የነገሥታት ፡ ልብ ፡ አይመረመርም ።
፬ ከብር ፡ ዝገትን ፡ አስወግድ ፥
ፈጽሞም ፡ ይጠራል ።
፭ ከንጉሥ ፡ ፊት ፡ ኃጥአንን ፡ አርቅ ፥
ዙፋኑም ፡ በጽድቅ ፡ ትጸናለች ።
፮ በንጉሥ ፡ ፊት ፡ አትመካ ፥
በታላላቆችም ፡ ስፍራ ፡ አትቁም ፤
፯ ዓይኖችህ ፡ ባዩት ፡ በመኰንን ፡ ፊት ፡ ከምትዋረድ ፡—
ወደዚህ ፡ ከፍ ፡ በል ፡ ብትባል ፡ ይሻልሃልና ።

፰ ባልንጀራህ ፡ ባሳፈረህ ፡ ጊዜ ፡ ኋላ ፡ እንዳትጸጸት ፡
ለክርክር ፡ ፈጥነህ ፡ አትውጣ ።
፱ ክርክርህን ፡ ከባልንጀራህ ፡ ጋር ፡ ተከራከር ፤
የሌላ ፡ ሰው ፡ ምሥጢር ፡ ግን ፡ አትግለጥ ፥
፲ የሚሰማ ፡ እንዳይነቅፍህ ፥
አንተንም ፡ ከማነወር ፡ ዝም ፡ እንዳይል ።

፲፩ የወርቅ ፡ እንኮይ ፡ በብር ፡ ፃሕል ፡ ላይ ፤
የጊዜው ፡ ቃል ፡ እንዲሁ ፡ ነው ።
፲፪ የምትሰማን ፡ ጆሮ ፡ የሚዘልፍ ፡ ጠቢብ ፡ ሰው ፡
እንደ ፡ ወርቅ ፡ ጉትቻ ፡ እንደሚያንጸባርቅም ፡ ዕንቍ ፡ እንዲሁ ፡ ነው ።
፲፫ በመከር ፡ ወራት ፡ የውርጭ ፡ ጠል ፡ ደስ ፡ እንደሚያሰኝ ፥
እንዲሁ ፡ የታመነ ፡ መልእክተኛ ፡ ለላኩት ፡ ነው ፤
የጌቶቹን ፡ ነፍስ ፡ ያሳርፋልና ።
፲፬ ስለ ፡ ስጦታው ፡ በሐሰት ፡ የሚመካ ፡ ሰው ፡
ዝናብ ፡ እንደማይከተለው ፡ ደመና ፡ ነፋስም ፡ ነው ።

፲፭ በትዕግሥት ፡ አለቃ ፡ ይለዝባል ፥
የገራም ፡ ምላስ ፡ አጥንትን ፡ ይሰብራል ።
፲፮ አጥብቀህ ፡ እንዳትጠግብ ፡ እንዳትተፋውም ፡
ማር ፡ በገኘህ ፡ ጊዜ ፡ የሚበቃህን ፡ ብላ ።
፲፯ እንዳይሰለችህ ፡ እንዳይጠላህም ፡
እግርህን ፡ ወደ ፡ ባልንጀራህ ፡ ቤት ፡ አታዘውትር ።
፲፰ በባልንጀራው ፡ በሐሰት ፡ የሚመሰክር ፡
እንደ ፡ መዶሻና ፡ እንደ ፡ ሰይፍ ፡ እንደ ፡ ተሳለም ፡ ፍላጻ ፡ ነው ።
፲፱ ወስላታውን ፡ ሰው ፡ በመከራ ፡ ጊዜ ፡ መተማመን ፡
እንደ ፡ ተሰበረ ፡ ጥርስና ፡ እንደ ፡ ሰለለ ፡ እግር ፡ ነው ።
፳ ለሚያዝን ፡ ልብ ፡ ዝማሬ ፡ የሚዘምር ፥
ለብርድ ፡ ቀን ፡ መጐናጸፊያውን ፡ እንደሚያስወግድ ፡
በቍስልም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ መጻጻ ፡ እንዲሁ ፡ ነው ።
፳፩ ጠላትህ ፡ ቢራብ ፡ እንጀራ ፡ አብላው ፥
ቢጠማም ፡ ውኃ ፡ አጠጣው ፤
፳፪ ፍም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ትሰበስባለህና ፥
እግዚአብሔርም ፡ ዋጋህን ፡ ይመልስልሃልና ።
፳፫ የሰሜን ፡ ነፋስ ፡ ወጀብ ፡ ያመጣል ፤
ሐሜተኛ ፡ ምላስም ፡ የሰውን ፡ ፊት ፡ ያስቈጣል ።
፳፬ ከጠበኛ ፡ ሴት ፡ ጋር ፡ በአንድ ፡ ቤት ፡ ከመቀመጥ ፡
በሰገነት ፡ ማዕዘን ፡ መቀመጥ ፡ ይሻላል ።
፳፭ የቀዘቀዘ ፡ ውኃ ፡ ለተጠማች ፡ ነፍስ ፡ ደስ ፡ እንደሚያሰኝ ፥

ከሩቅ ፡ አገር ፡ የመጣ ፡ መልካም ፡ ምስራች ፡ እን
ዲሁ ፡ ነው ።
፳፮ ፡ በኀጥእ ፡ ፊት ፡ የሚወድቅ ፡ ጻድቅ ፡
እንደ ፡ ደፈረሰ ፡ ፈሳሽና ፡ እንደ ፡ ረከሰ ፡ ምንጭ ፡
ነው ።
፳፯ ፡ ብዙ ፡ ማር ፡ መብላት ፡ መልካም ፡ አይደለም ፤
እንዲሁም ፡ የራስን ፡ ክብር ፡ መፈላለግ ፡ አያስ
ከብርም ።
፳፰ ፡ ቅጥር ፡ እንደሌላት ፡ እንደ ፡ ፈረሰች ፡ ከተማ ፥
መንፈሱን ፡ የማይከለክል ፡ ሰው ፡ እንዲሁ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ። (፪)

፩ ፡ በረዶ ፡ በበጋ ፡ ዝናብም ፡ በመከር ፡ እንዳይገባ ፥
እንዲሁ ፡ ለሰነፍ ፡ ክብር ፡ አይገባውም ።
፪ ፡ እንደሚተላለፍ ፡ ድንቢጥ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህም ፡
እንደሚበርር ፡ ጨረባ ፥
እንዲሁ ፡ ከንቱ ፡ እርግማን ፡ በማንም ፡ ላይ ፡ አይ
ደርስም ።
፫ ፡ አለንጋ ፡ ለፈረስ ፥ ልጓም ፡ ለአህያ ፥
በትርም ፡ ለሰነፍ ፡ ጀርባ ፡ ነው ።
፬ ፡ አንተ ፡ ደግሞ ፡ እርሱን ፡ እንዳትመስል ፡
ለሰነፍ ፡ እንደ ፡ ስንፍናው ፡ አትመልስለት ።
፭ ፡ ለራሱ ፡ ጠቢብ ፡ የሆነ ፡ እንዳይመስለው ፡
ለሰነፍ ፡ እንደ ፡ ስንፍናው ፡ መልስለት ።
፮ ፡ በሰነፍ ፡ መልእክተኛ ፡ እጅ ፡ ነገርን ፡ የሚልክ ፡
እግሮቹን ፡ ይቈርጣል ፡ ግፍንም ፡ ይጠጣል ።
፯ ፡ እንደሚንጠለጠሉ ፡ የአንካሳ ፡ እግሮች ፥
እንዲሁም ፡ ምሳሌ ፡ በሰነፎች ፡ አፍ ፡ ነው ።
፰ ፡ ለሰነፍ ፡ ክብርን ፡ የሚሰጥ ፡
ድንጋይን ፡ በወንጭፍ ፡ እንደሚያስር ፡ ነው ።
፱ ፡ እሾህ ፡ በሰካር ፡ እጅ ፡ እንደሚሰካ ፥
እንዲሁ ፡ ምሳሌ ፡ በሰነፎች ፡ አፍ ፡ ነው ።
፲ ፡ ዋና ፡ ሠራተኛ ፡ ሁሉን ፡ ነገር ፡ ይሠራል ፤
ሰነፍን ፡ የሚቀጥር ፡ ግን ፡ መንገድ ፡ አላፊውን ፡
እንደሚቀጥር ፡ ነው ።
፲፩ ፡ ወደ ፡ ትፋቱ ፡ እንደሚመለስ ፡ ውሻ ፡
ስንፍናውን ፡ የሚደግም ፡ ሰው ፡ እንዲሁ ፡ ነው ።
፲፪ ፡ ለራሱ ፡ ጠቢብ ፡ የሆነ ፡ የሚመስለውን ፡ ሰው ፡
አየኸውን ?
ከእርሱ ፡ ይልቅ ፡ ለሰነፍ ፡ ተስፋ ፡ አለው ።
፲፫ ፡ ታካች ፡ ሰው ፡— አንበሳ ፡ በመንገድ ፡ አለ ፤
አንበሳ ፡ በጎዳና ፡ አለ ፡ ይላል ።
፲፬ ፡ ማንቃ ፡ በማጠፊያው ፡ ላይ ፡ እንደሚዞር ፥
እንዲሁ ፡ ታካች ፡ ሰው ፡ በአልጋው ፡ ላይ ፡ ይመላ
ለሳል ።
፲፭ ፡ ታካች ፡ ሰው ፡ እጁን ፡ ወደ ፡ ወጭት ፡ ያጠል
ቃል ፤
ወደ ፡ አፉም ፡ ይመልሳት ፡ ዘንድ ፡ ለእርሱ ፡
ድካም ፡ ነው ።
፲፮ ፡ ታካች ፡ ሰው ፡ በጥበብ ፡ ከሚመልሱ ፡ ከሰባት ፡
ሰዎች ፡ ይልቅ ፡
ለራሱ ፡ ጠቢብ ፡ የሆነ ፡ ይመስለዋል ።
፲፯ ፡ አልፎ ፡ በሌላው ፡ ጥል ፡ የሚደባለቅ ፡
ውሻን ፡ በጅራቱ ፡ እንደሚይዝ ፡ ነው ።
፲፰ ፡ ትንታግንና ፡ ፍላጻን ፡ ሞትንም ፡ እንደሚወረ
ውር ፡
እንደ ፡ ዕብድ ፡ ሰው ፥
፲፱ ፡ በልንጀራውን ፡ የሚያታልል ፡—
በጨዋታ ፡ አደረግሁት ፡ የሚል ፡ ሰውም ፡ እን
ዲሁ ፡ ነው ።
፳ ፡ እንጨት ፡ በለቀ ፡ ጊዜ ፡ እሳት ፡ ይጠፋል ፤
ጆሮ ፡ ጠቢ ፡ በሌለበትም ፡ ዘንድ ፡ ጠብ ፡ ጸጥ ፡
ይላል ።
፳፩ ፡ ከሰል ፡ ፍምን ፡ እንጨትም ፡ እሳትን ፡ እንዲያበዛ ፥
እንዲሁ ፡ ቍጡ ፡ ሰው ፡ ጠብን ፡ ያበዛል ።
፳፪ ፡ የጆሮ ፡ ጠቢ ፡ ቃል ፡ እንደ ፡ ጣፋጭ ፡ መብል ፡
ነው ፥
እርሱም ፡ እስከ ፡ ሆድ ፡ ጕርጆች ፡ ድረስ ፡ ይወር
ዳል ።
፳፫ ፡ ክፋት ፡ በልቡ ፡ ሳለ ፡ ፍቅርን ፡ የሚናገር ፡ ከንፈር ፡
በብር ፡ ዝገት ፡ እንደ ፡ ተለበጠ ፡ የሸክላ ፡ ዕቃ ፡
ነው ።
፳፬ ፡ ጠላት ፡ በከንፈሩ ፡ ተስፋ ፡ ይሰጣል ፥
በልቡ ፡ ግን ፡ ተንኰልን ፡ ያኖራል ።
፳፭ ፡ በልቡ ፡ ሰባት ፡ ርኵሰት ፡ አለበትና ፡
በቃሉ ፡ አሳምሮ ፡ ቢናገርህ ፡ አትመነው ።
፳፮ ፡ ጠላትነቱን ፡ በተንኰል ፡ የሚሸሽግ ፥
ክፋቱ ፡ በጉባኤ ፡ መካከል ፡ ይገለጣል ።
፳፯ ፡ ጕድጓድን ፡ የሚምስ ፡ ይወድቅበታል ፤
ድንጋይንም ፡ የሚያንከባልል ፡ ይገለበጥበታል ።
፳፰ ፡ ሐሰተኛ ፡ ምላስ ፡ ያቈሰላቸውን ፡ ሰዎች ፡ ይጠ
ላል ፤
ልዝብ ፡ አፍም ፡ ጥፋትን ፡ ያመጣል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ። (፫)

፩ ፡ ቀን ፡ የሚያመጣውን ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አታ
ውቅምና ፡
ነገ ፡ በሚሆነው ፡ አትመካ ።
፪ ፡ ሌላ ፡ ያመስግንህ ፡ እንጂ ፡ አፍህ ፡ አይደለም ፤
በዕድ ፡ ሰው ፡ እንጂ ፡ ከንፈርህ ፡ አይደለም ።
፫ ፡ ድንጋይ ፡ ከባድ ፡ ነው ፡ አሸዋም ፡ ሸክሙ ፡ ጽኑ ፡
ነው ፤
ከሁለቱ ፡ ግን ፡ የሰነፍ ፡ ቍጣ ፡ ይከብዳል ።
፬ ፡ ቍጣ ፡ ምሕረት ፡ የሌለው ፡ ነው ፥ መዓትም ፡
እንደ ፡ ጎርፍ ፡ ነው ፤
በቅንዓት ፡ ፊት ፡ ግን ፡ ማን ፡ ይቆማል ?
፭ ፡ የተገለጠ ፡ ዘለፋ ፡
ከተሰወረ ፡ ፍቅር ፡ ይሻላል ።
፮ ፡ የወዳጅ ፡ ማቍሰል ፡ የታመነ ፡ ነው ፤
የጠላት ፡ መሳም ፡ ግን ፡ የበዛ ፡ ነው ።
፯ ፡ የጠገበች ፡ ነፍስ ፡ የማር ፡ ወለላ ፡ ትረግጣለች ፤
ለተራበች ፡ ነፍስ ፡ ግን ፡ የመረረ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡
ይጣፍጣታል ።
፰ ፡ ስፍራውን ፡ የሚተው ፡ ሰው ፡
ቤቱን ፡ ትቶ ፡ እንደሚበርር ፡ ወፍ ፡ ነው ።
፱ ፡ ሽቱና ፡ ዕጣን ፡ ልብን ፡ ደስ ፡ ያሰኛሉ ፤
እንዲሁ ፡ ነፍስ ፡ በወዳጅ ፡ ምክር ፡ ደስ ፡ ይላታል ።
፲ ፡ ወዳጅህንና ፡ የአባትህን ፡ ወዳጅ ፡ አትተው ፤

በመከራህም ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ወንድምህ ፡ ቤት ፡
አትግባ ፤
የቀረበ ፡ ወዳጅ ፡ ከራቀ ፡ ወንድም ፡ ይሻላል ።

፲፩ ልጄ ፡ ሆይ ÷ ጠቢብ ፡ ሁን ÷ ልቤንም ፡ ደስ ፡
አሰኘው ÷
ለሚሰድበኝ ፡ መልስ ፡ መስጠት ፡ ይቻለኛል ፡ ዘንድ ።
፲፪ ብልህ ፡ ሰው ፡ ክፉን ፡ አይቶ ፡ ይሸሸጋል ፤
አላዋቂዎች ፡ ግን ፡ አልፈው ፡ ይጐዳሉ ።
፲፫ ለማያውቀው ፡ ከተዋሰ ፡ ሰው ፡ ልብሱን ፡ ውሰድ ÷
ለእንግዳ ፡ የተዋሰውንም ፡ እርሱን ፡ አግተው ።
፲፬ ባልንጀራውን ፡ በታላቅ ፡ ቃል ፡ ማለዳ ፡ የሚባ
ርክ ፡ ሰው ፡
እንደሚራገም ፡ ያህል ፡ ነው ።
፲፭ በዝናብ ፡ ቀን ፡ የሚያንጠባጥብ ፡ ቤትና ፡ ጠበኛ ፡
ሴት ፡ አንድ ፡ ናቸው ፤
፲፮ እርስዋንም ፡ መከልከል ፡
ነፋስን ፡ መከልከልና ፡ ዘይትን ፡ በቀኝ ፡ እጅ ፡
መጨበጥ ፡ ነው ።
፲፯ ብረት ፡ ብረትን ፡ ይስለዋል ÷
ሰውም ፡ ባልንጀራውን ፡ ይስላል ።
፲፰ በለሱን ፡ የጠበቀ ፡ ፍሬዋን ፡ ይበላል ÷
ጌታውንም ፡ የሚጠብቅ ፡ ይከብራል ።
፲፱ ፊት ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡ ለፊት ፡ እንደሚታይ ÷
እንዲሁ ፡ የሰው ፡ ልብ ፡ ለሰው ፡ ይታያል ።
፳ ሲኦልና ፡ ጥፋት ፡ እንዳይጠግቡ ÷
እንዲሁ ፡ የሰው ፡ ዓይን ፡ አይጠግብም ።
፳፩ ብር ፡ በከውር ፡ ወርቅም ፡ በማቅለጫ ፡ ይፈተ
ናል ፤
ሰውም ፡ በሚያመሰግኑት ፡ ሰዎች ፡ አፍ ፡ ይፈ
ተናል ።
፳፪ ሰነፍን ፡ በሙቀጫ ፡ ውስጥ ፡ ከእህል ፡ ጋር ፡
በዘነዘና ፡ ብትወቅጠው ÷
ስንፍናው ፡ ከእርሱ ፡ አይርቅም ።

፳፫ የበጎችህን ፡ መልክ ፡ አስተውለህ ፡ እወቅ ÷
በከብቶችህም ፡ ላይ ፡ ልብህን ፡ አኑር ፤
፳፬ ባለጠግነት ፡ ለዘላለም ፡ አይኖርምና ÷
ዘውድም ፡ ለትውልድ ፡ ሁሉ ፡ አይጸናምና ።
፳፭ ደረቅ ፡ ሣር ፡ በታጨደ ፡ ጊዜ ÷ አዲስ ፡ ለምለም ፡
በታየ ፡ ጊዜ ÷
ከተራራውም ፡ ቡቃያ ፡ በተሰበሰበ ፡ ጊዜ ÷
፳፮ በጎች ፡ ለልብስህ ፡
ፍየሎችም ፡ የእርሻ ፡ ዋጋ ፡ ይሆናሉ ።
፳፯ ለሲሳይህ ፡ ለቤተ ፡ ሰቦችህም ፡ ሲሳይ ፡
ለገረዶችህም ፡ ምግብ ፡ የፍየል ፡ ወተት ፡ ይበ
ቃል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ። (፬)

፩ ኀጥእ ፡ ማንም ፡ ሳያሳድደው ፡ ይሸሻል ፤
ጻድቅ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ያለ ፡ ፍርሃት ፡
ይኖራል ።
፪ ስለ ፡ አገሪቱ ፡ ዓመፀኝነት ፡ አለቆችዋ ፡ ብዙ ፡
ሆኑ ፤
በአስተዋይና ፡ በአዋቂ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ዘመንዋ ፡
ይረዝማል ።
፫ ድሆችን ፡ የሚያስጨንቅ ፡ ምስኪን ፡ ሰው ፡
እህልን ፡ እንደሚያጠፋ ፡ እንደ ፡ ዶፍ ፡ ዝናብ ፡
ነው ።
፬ ሕግን ፡ የሚተዉ ፡ ሰዎች ፡ ኀጥኣንን ፡ ያመሰግ
ናሉ ፤
ሕግ ፡ ጠባቂዎች ፡ ግን ፡ ይጣሉአቸዋል ።
፭ ክፉዎች ፡ ሰዎች ፡ ፍርድን ፡ አያስተውሉም ፤
እግዚአብሔርን ፡ የሚሹ ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡ ያስተ
ውላሉ ።
፮ በጠማማ ፡ መንገድ ፡ ከሚሄድ ፡ ባለጠጋ ፡
ያለ ፡ ነውር ፡ የሚሄድ ፡ ድሀ ፡ ይሻላል ።
፯ ሕግን ፡ የሚጠብቅ ፡ አስተዋይ ፡ ልጅ ፡ ነው ፤
ምናምንቴዎችን ፡ የሚከተል ፡ ግን ፡ አባቱን ፡
ያሳፍራል ።
፰ በአራጣ ፡ ብዛትና ፡ በቅሚያ ፡ ሀብቱን ፡ የሚያ
በዛ ፡
ለድሀ ፡ ለሚራራ ፡ ያከማችለታል ።
፱ ሕግን ፡ ከመስማት ፡ ጆሮውን ፡ የሚመልስ ፡
ጸሎቱ ፡ አስጸያፊ ፡ ናት ።
፲ ቅኖችን ፡ በክፉ ፡ መንገድ ፡ የሚያስት ÷
እርሱ ፡ ወደ ፡ ጕድጓዱ ፡ ይወድቃል ፤
ፍጹማን ፡ ግን ፡ መልካም ፡ ነገርን ፡ ይወርሳሉ ።
፲፩ ባለጠጋ ፡ ሰው ፡ ለራሱ ፡ ጠቢብ ፡ የሆነ ፡ ይመስ
ለዋል ፤
አስተዋይ ፡ ድሀ ፡ ግን ፡ ይመረምረዋል ።
፲፪ ጻድቃን ፡ ድል ፡ በደረጉ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ ክብር ፡
አለ ፤
ኀጥኣን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ባሉ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ሰው ፡
ይሸሸጋል ።
፲፫ ኀጢአቱን ፡ የሚሰውር ፡ አይለማም ፤
የሚናዘዝበትና ፡ የሚተዋት ፡ ግን ፡ ምሕረትን ፡
ያገኛል ።
፲፬ ሁልጊዜ ፡ የሚፈራ ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ፤
ልቡን ፡ የሚያጸና ፡ ግን ፡ በክፉ ፡ ላይ ፡ ይወድ
ቃል ።
፲፭ በድሀ ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ የሚገዛ ፡ ክፉ ፡ መኰንን ፡
እንደሚያገሣ ፡ አንበሳና ፡ እንደ ፡ ተራበ ፡ ድብ ፡
ነው ።
፲፮ አእምሮ ፡ የጐደለው ፡ መኰንን ፡ ትልቅ ፡ ግፈኛ ፡
ነው ፤
ግፍን ፡ የሚጠላ ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ይኖራል ።
፲፯ የሰው ፡ ደም ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ እስከ ፡ ጕድጓድ ፡
ይሸሻል ÷
ማንም ፡ አያስጠጋውም ።
፲፰ በቅንነት ፡ የሚሄድ ፡ ይድናል ፤
በጠማምነት ፡ የሚሄድ ፡ ግን ፡ ወዲያው ፡ ይወ
ድቃል ።
፲፱ ምድሩን ፡ የሚያርስ ፡ እንጀራ ፡ ይጠግባል ፤
ምናምንቴዎችን ፡ የሚከተል ፡ ግን ፡ ድህነት ፡
ይሞላበታል ።
፳ የታመነ ፡ ሰው ፡ እጅግ ፡ ይባረካል ፤
ባለጠጋ ፡ ለመሆን ፡ የሚቸኵል ፡ ግን ፡ ሳይቀጣ ፡

አይቀርም ።

፳፩፤ ማድላት ፥ በቍራሽ ፡ እንጀራም ፡ መበደል ፡ መልካም ፡ አይደለም ።

፳፪፤ ምቀኛ ፡ ሰው ፡ ባለጠጋ ፡ ለመሆን ፡ ይቸኵላል ፡ ችጋርም ፡ እንደሚመጣበት ፡ አያውቅም ።

፳፫፤ ምላሱን ፡ ከሚያጣፍጥ ፡ ይልቅ ፡ ሰውን ፡ የሚገሥጽ ፡ በኋላ ፡ ሞገስ ፡ ያገኛል ።

፳፬፤ ከአባቱና ፡ ከእናቱ ፡ የሚሰርቅ ፡— ኃጢአትን ፡ አልሠራሁም ፡ የሚልም ፡ የአጥፊ ፡ ባልንጀራ ፡ ነው ።

፳፭፤ የሚጐመጅ ፡ ሰው ፡ ክርክርን ፡ ያነሣሣል ፤ በእግዚአብሔር ፡ የሚታመን ፡ ግን ፡ ይጠግባል ።

፳፮፤ በገዛ ፡ ልቡ ፡ የሚታመን ፡ ሰው ፡ ሰነፍ ፡ ነው ፤ በጥበብ ፡ የሚሄድ ፡ ግን ፡ ይድናል ።

፳፯፤ ለድሀ ፡ የሚሰጥ ፡ አያጣም ፤ ዓይኖቹን ፡ የሚጨፍን ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ይረገማል ።

፳፰፤ ኀጥአን ፡ በተነሡ ፡ ጊዜ ፡ ሰዎች ፡ ይሸሸጋሉ ፤ እነርሱ ፡ በጠፉ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ጻድቃን ፡ ይበዛሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ። (፭)

፩፤ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ተዘልፎ ፡ አንገቱን ፡ ያደነደነ ፡ ድንገት ፡ ይሰበራል ፥ ፈውስም ፡ የለውም ።

፪፤ ጻድቃን ፡ በበዙ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝብ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤ ኀጥአን ፡ በሠለጠኑ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ሕዝብ ፡ ያለቅሳል ።

፫፤ ጥበብን ፡ የወደደ ፡ ሰው ፡ አባቱን ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፤ ጋለሞቶችን ፡ የሚከተል ፡ ግን ፡ ሀብቱን ፡ ያጠፋል ።

፬፤ ንጉሥ ፡ በፍርድ ፡ አገሩን ፡ ያጸናል ፤ መማለጃ ፡ የሚወድድ ፡ ግን ፡ ያፈርሰዋል ።

፭፤ ወዳጁን ፡ በለዘበ ፡ ቃል ፡ የሚናገር ፡ ሰው ፡ ለእግሩ ፡ መርበብን ፡ ይዘረጋል ።

፮፤ በክፉ ፡ ሰው ፡ ዓመፃ ፡ ወጥመድ ፡ ይገኛል ፤ ጻድቅ ፡ ግን ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፥ እልልም ፡ ይላል ።

፯፤ ጻድቅ ፡ የድሆችን ፡ ፍርድ ፡ ይመለከታል ፤ ኀጥእ ፡ ግን ፡ እውቀትን ፡ አያስተውልም ።

፰፤ ፌዘኞች ፡ ከተማቸውን ፡ ያቃጥላሉ ፤ ጠቢባን ፡ ግን ፡ ቍጣን ፡ ይመልሳሉ ።

፱፤ ጠቢብ ፡ ከሰነፍ ፡ ጋር ፡ ቢጣላ ፥ ሰነፉ ፡ ወይም ፡ ይቈጣል ፡ ወይም ፡ ይስቃል ፥ ዕረፍትም ፡ የለም ።

፲፤ ደምን ፡ ለማፍሰስ ፡ የሚሹ ፡ ሰዎች ፡ ፍጹሙን ፡ ሰው ፡ ይጠላሉ ፥ ደግሞም ፡ የቅኑን ፡ ሰው ፡ ነፍስ ፡ ይሻሉ ።

፲፩፤ ሰነፍ ፡ ሰው ፡ ቍጣውን ፡ ሁሉ ፡ ያወጣል ፤ ጠቢብ ፡ ግን ፡ በውስጡ ፡ ያስቀረዋል ።

፲፪፤ መኰንን ፡ ሐሰተኛ ፡ ነገርን ፡ ቢያደምጥ ፥ ከእርሱ ፡ በታች ፡ ያሉት ፡ ሁሉ ፡ ዓመፀኞች ፡ ይሆናሉ ።

፲፫፤ ድሀና ፡ ግፈኛ ፡ ተገናኙ ፤ እግዚአብሔር ፡ የሁለቱንም ፡ ዓይን ፡ ያበራል ።

፲፬፤ ለድሀ ፡ በእውነት ፡ የሚፈርድ ፡ ንጉሥ ፥ ዙፋኑ ፡ ለዘላለም ፡ ይጸናል ።

፲፭፤ በትርና ፡ ተግሣጽ ፡ ጥበብን ፡ ይሰጣሉ ፤ ያልተቀጣ ፡ ብላቴና ፡ ግን ፡ እናቱን ፡ ያሳፍራል ።

፲፮፤ ኀጥአን ፡ ሲበዙ ፡ ኃጢአት ፡ ትበዛለች ፤ ጻድቃን ፡ ግን ፡ ውድቀታቸውን ፡ ያያሉ ።

፲፯፤ ልጅህን ፡ ቅጣ ፡ ዕረፍትንም ፡ ይሰጥሃል ፤ ለነፍስህም ፡ ተድላን ፡ ይሰጣታል ።

፲፰፤ ራእይ ፡ ባይኖር ፡ ሕዝብ ፡ መረን ፡ ይሆናል ፤ ሕግን ፡ የሚጠብቅ ፡ ግን ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ።

፲፱፤ ባሪያ ፡ በቃል ፡ አይገሠጽም ፤ ቢያስተውል ፡ እንኳ ፡ አይመልስምና ።

፳፤ በቃሉ ፡ የሚቸኵለውን ፡ ሰው ፡ ብታይ ፥ ከእርሱ ፡ ይልቅ ፡ ለሰነፍ ፡ ተስፋ ፡ አለው ።

፳፩፤ ባሪያውን ፡ ከሕፃንነቱ ፡ ጀምሮ ፡ በማቀማጠል ፡ የሚያሳድግ ፡ የኋላ ፡ ኋላ ፡ እንደ ፡ ጌታ ፡ ያደርገዋል ።

፳፪፤ ቍጡ ፡ ሰው ፡ ክርክርን ፡ ያነሣሣል ፥ ወፈፍተኛ ፡ ሰውም ፡ ኃጢአትን ፡ ያበዛል ።

፳፫፤ ሰውን ፡ ትዕቢቱ ፡ ያዋርደዋል ፤ መንፈሱን ፡ የሚያዋርድ ፡ ግን ፡ ክብርን ፡ ይቀበላል ።

፳፬፤ ከሌባ ፡ ጋር ፡ የሚካፈል ፡ ነፍሱን ፡ ይጠላል ፤ መርገምን ፡ ይሰማል ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ምንም ፡ አይገልጥም ።

፳፭፤ ሰውን ፡ መፍራት ፡ ወጥመድ ፡ ያመጣል ፤ በእግዚአብሔር ፡ የሚታመን ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ ይጠበቃል ።

፳፮፤ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ የሹምን ፡ ፊት ፡ ይሻሉ ፤ የሰው ፡ ፍርድ ፡ ግን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

፳፯፤ ኃጢአተኛ ፡ በጻድቃን ፡ ዘንድ ፡ አስጸያፊ ፡ ነው ፤ በቀና ፡ መንገድ ፡ የሚሄደውም ፡ በኀጥአን ፡ ዘንድ ፡ አስጸያፊ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ። (፯)

፩፤ የማሣ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ የያቄ ፡ ልጅ ፡ የአጉር ፡ ቃል ። ሰውዮው ፡ ለኢቲኤልና ፡ ለኡካል ፡ እንደዚህ ፡ ይናገራል ፡—

፪፤ እኔ ፡ በእውነት ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ደንቆሮ ፡ ነኝ ፥ የሰውም ፡ ማስተዋል ፡ የለብኝም ።

፫፤ ጥበብንም ፡ አልተማርሁም ፥ ቅዱሱንም ፡ አላወቅሁትም ።

፬፤ ወደ ፡ ሰማይ ፡ የወጣ ፡ የወረደስ ፡ ማን ፡ ነው ? ነፋስንስ ፡ በእጁ ፡ የጨበጠ ፡ ማን ፡ ነው ? ውኃንስ ፡ በልብሱ ፡ የቋጠረ ፡ ማን ፡ ነው ? የምድርን ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ ያጸና ፡ ማን ፡ ነው ? ይህን ፡ ታውቅ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፥ ስሙ ፡ ማን ፡ የልጁስ ፡ ስም ፡ ማን ፡ ነው ?

፭፤ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ተፈትናለች ፤ እርሱ ፡ ለሚታመኑት ፡ ጋሻ ፡ ነው ።

፮፤ እንዳይዘልፍህ ፥ ሐሰተኛም ፡ እንዳትሆን ፡ በቃሉ ፡ አንዳች ፡ አትጨምር ።

፯ ሁለትን ፡ ነገር ፡ ከአንተ ፡ እሻለሁ ÷
ሳልሞትም ፡ አትከልክለኝ ፤
፰ ከንቱነትንና ፡ ሐሰተኛነትን ፡ ከእኔ ፡ አርቃቸው ፤
ድህነትንና ፡ ባለጠግነትን ፡ አትስጠኝ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ የሚያስፈልገኝን ፡ እንጀራ ፡ ስጠኝ ÷
፱ እንዳልጠግብ ፡ እንዳልክድህም ፦
እግዚአብሔርስ ፡ ማን ፡ ነው ? እንዳልል ፤
ድሀም ፡ እንዳልሆን ፡ እንዳልሰርቅም ÷
በአምላኬም ፡ ስም ፡ በሐሰት ፡ እንዳልምል ።

፲ እንዳይሰድብህ ፡ በደለኛም ፡ እንዳትሆን ፡
ባሪያን ፡ በጌታው ፡ ፊት ፡ አትማ ።

፲፩ አባቱን ፡ የሚረግም ÷
እናቱንም ፡ የማይባርክ ፡ ትውልድ ፡ አለ ።
፲፪ ለራሱ ፡ ንጹሕ ፡ የሆነ ፡ የሚመስለው ፡
ከርኵሰቱ ፡ ያልጠራ ፡ ትውልድ ፡ አለ ።
፲፫ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያሉ ፡ ዓይኖች ፡ ያሉት ÷
ሽፋሽፍቶቹም ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ የሚያዩ ፡ ትውልድ ፡ አለ ።
፲፬ ድሆችን ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ ችግረኞችንም ፡ ከሰው ፡ መካከል ፡ ያጠፋና ፡ ይጨርስ ፡ ዘንድ ፡
ጥርሶቹ ፡ ሰይፍ ፡ መንጋጎቹም ፡ ካራ ፡ የሆኑ ፡ ትውልድ ፡ አለ ።

፲፭ አልቅት ፦ ስጠን ፡ ስጠን ፡ የሚሉ ፡ ሁለት ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ አሉት ።
ሦስቱ ፡ የማይጠግቡ ፡ አራቱም ፦ በቃን ፡ የማይሉ ፡ ናቸው ፤
፲፮ እነርሱም ፡ ሲኦልና ፡ የማትወልድ ፡ ማኅፀን ÷
ውኃ ፡ የማትጠግብ ፡ ምድርና ፦
በቃኝ ፡ የማትል ፡ እሳት ፡ ናቸው ።

፲፯ በአባትዋ ፡ የምታላግጥን ፡
የእናትዋንም ፡ ትእዛዝ ፡ የምትንቅን ፡ ዓይን ፡
የሸለቆ ፡ ቍራዎች ፡ ይጐጠጕጡአታል ÷
አሞራዎችም ፡ ይበሉአታል ።

፲፰ ሦስት ፡ ነገር ፡ ይገርመኛል ÷
አራተኛውንም ፡ ከቶ ፡ አላስተውለውም ።
፲፱ እነርሱም ፡ የንስር ፡ መንገድ ፡ በሰማይ ÷
የእባብ ፡ መንገድ ፡ በድንጋይ ፡ ላይ ÷
የመርከብ ፡ መንገድ ፡ በባሕር ፡ ላይ ÷
የሰውም ፡ መንገድ ፡ ከቈንጆ ፡ ጋር ፡ ናቸው ።
፳ እንዲሁ ፡ በልታ ፡ አፍዋን ፡ የምታብስ ፦
አንዳች ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አላደረግሁም ፡ የምትልም ፡
የአመንዝራ ፡ ሴት ፡ መንገድ ፡ ናት ።

፳፩ በሦስት ፡ ነገር ፡ ምድር ፡ ትናወጣለች ÷
አራተኛውንም ፡ ትሸከም ፡ ዘንድ ፡ አይቻላትም ።
፳፪ ባሪያ ፡ በነገሠ ፡ ጊዜ ÷
ሰነፍም ፡ እንጀራ ፡ በጠገበ ፡ ጊዜ ÷
፳፫ የተጠላች ፡ ሴት ፡ ባል ፡ በገኘች ፡ ጊዜ ÷
ሴት ፡ ባሪያም ፡ እመቤቷን ፡ በወረሰች ፡ ጊዜ ።

፳፬ በምድር ፡ ላይ ፡ አራት ፡ ጥቃቅን ፡ ፍጥረቶች ፡ አሉ ፤
እነርሱ ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ጠቢባን ፡ ናቸው ፤
፳፭ ገብረ ፡ ጕንዳን ፡ ኃይል ፡ የሌላቸው ፡ ሕዝቦች ፡ ናቸው ÷
ነገር ፡ ግን ፡ በበጋ ፡ መኖዋቸውን ፡ ይሰበስባሉ ።
፳፮ ሽኮኮዎች ፡ ያልበረቱ ፡ ሕዝቦች ፡ ናቸው ÷
ቤታቸውን ፡ ግን ፡ በቋጥኝ ፡ ድንጋይ ፡ ውስጥ ፡ ያደርጋሉ ።
፳፯ አንበጣዎች ፡ ንጉሥ ፡ የላቸውም ÷
ሁላቸው ፡ ግን ፡ በመልካም ፡ ሥርዓት ፡ ይሄዳሉ ።
፳፰ እንሽላሊት ፡ በእጅ ፡ ይያዛል ÷
በነገሥታት ፡ ግቢ ፡ ግን ፡ ይኖራል ።

፳፱ መልካም ፡ አረማመድን ፡ የሚራመዱ ፡ ሦስት ፡ ፍጥረቶች ፡ አሉ ÷
አራተኛውም ፡ መልካም ፡ አካሄድን ፡ ይሄዳል ፤
፴ የአንበሳ ፡ ደቦል ፡ ከእንስሳ ፡ ሁሉ ፡ የሚበረታ ÷
የማይመለስ ÷ እንስሳንም ፡ የማይፈራ ፤
፴፩ በእንስቶች ፡ መካከል ፡ በድፍረት ፡ የሚራመድ ፡ አውራ ፡ ዶሮ ፤
መንጋን ፡ የሚመራ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፤
በሕዝብ ፡ ፊት ፡ በግልጥ ፡ የሚናገር ፡ ንጉሥ ።

፴፪ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ስትል ፡ ስንፍናን ፡ ያደረግህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷
ክፉም ፡ ያሰብህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷
እጅህን ፡ በአፍህ ፡ ላይ ፡ ጫን ።
፴፫ ወተት ፡ መግፋት ፡ ቅቤን ፡ ያወጣል ÷
አፍንጫንም ፡ መጭመቅ ፡ ደምን ፡ ያወጣል ፤
እንዲሁም ፡ ቍጣን ፡ መጐተት ፡ ጠብን ፡ ያወጣል ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፩ ። (፯)

፩ እናቱ ፡ እርሱን ፡ ያስተማረችበት ፡ የማሣ ፡ ንጉሥ ፡ የልሙኤል ፡ ቃል ።
፪ ልጄ ፡ ሆይ ÷ ምንድር ፡ ነው ? የሆዴ ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ምንድር ፡ ነው ?
የስእለቴ ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ምንድር ፡ ነው ?
፫ ጕልበትህን ፡ ለሴቶች ፡ አትስጥ ÷
መንገድህንም ፡ ነገሥታትን ፡ ለሚያጠፉ ።
፬ ለነገሥታት ፡ አይገባም ÷ ልሙኤል ፡ ሆይ ÷ ነገሥታት ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ይጠጡ ፡ ዘንድ ፡ አይገባም ÷
መሳፍንትም ፦ ብርቱ ፡ መጠጥ ፡ ወዴት ፡ ነው ? ይሉ ፡ ዘንድ ፤
፭ እንዳይጠጡና ፡ ሕግን ፡ እንዳይረሱ ÷
የድሀ ፡ ልጆችንም ፡ ፍርድ ፡ እንዳያጐድሉ ።
፮ ለጥፋት ፡ ለቀረበው ፡ ሰው ፡ ብርቱ ፡ መጠጥ ፡ ስጡት ÷
ነፍሱ ፡ ለመረረውም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ስጡት ፤
፯ ይጠጣ ፡ ድህነቱንም ፡ ይርሳ ÷
ጕስቍልናውንም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አያስብ ።
፰ አፍህን ፡ ስለ ፡ ዲዳው ፡ ክፈት ÷
ተስፋ ፡ ስለሌላቸውም ፡ ሁሉ ፡ ተፋረድ ።

፱፤ አፍህን ፡ ክፈት ፥ በእውነትም ፡ ፍረድ ፤
ለድሀና ፡ ለምስኪን ፡ ፍረድ ።

፲፤ ልባም ፡ ሴትን ፡ ማን ፡ ሊያገኛት ፡ ይችላል ?
ዋጋዋ ፡ ከቀይ ፡ ዕንቍ ፡ እጅግ ፡ ይበልጣል ።
፲፩፤ የባልዋ ፡ ልብ ፡ ይታመንባታል ፥
ምርኮም ፡ አይጐድልበትም ።
፲፪፤ ዕድሜዋን ፡ሙሉ ፡ መልካም ፡ ታደርግለታለች ፥
ክፉም ፡ አታደርግም ።
፲፫፤ የበግ ፡ ጠጕርና ፡ የተልባ ፡ እግር ፡ ትፈልጋለች ፥
በእጆችዋም ፡ ደስ ፡ ብሎአት ፡ ትሠራለች ።
፲፬፤ እርስዋ ፡ እንደ ፡ ነጋዴ ፡ መርከብ ፡ ናት ፤
ከሩቅ ፡ አገር ፡ ምግብዋን ፡ ትሰበስባለች ።
፲፭፤ ገና ፡ ሌሊት ፡ ሳለ ፡ ትነሣለች ፡
ለቤትዋም ፡ ሰዎች ፡ ምግባቸውን ፥
ለገረዶችዋም ፡ ተግባራቸውን ፡ ትሰጣለች ።
፲፮፤ እርሻንም ፡ ተመልክታ ፡ ትገዛለች ፤
ከእጅዋም ፡ ፍሬ ፡ ወይን ፡ ትተክላለች ።
፲፯፤ ወገብዋን ፡ በኃይል ፡ ትታጠቃለች ፥
ክንድዋንም ፡ ታበረታለች ።
፲፰፤ ንግድዋ ፡ መልካም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ትመለከታለች ፤
መብራትዋ ፡ በሌሊት ፡ አይጠፋም ።
፲፱፤ እጅዋን ፡ ወደ ፡ አመልማሎ ፡ ትዘረጋለች ፥
ጣቶችዋም ፡ እንዝርትን ፡ ይይዛሉ ።
፳፤ እጅዋን ፡ ወደ ድሀ ፡ ትዘረጋለች ፥
ወደ ፡ ችግረኛም ፡ እጅዋን ፡ ትሰድዳለች ።
፳፩፤ ለቤትዋ ፡ ሰዎች ፡ ከበረዶ ፡ ብርድ ፡ የተነሣ ፡ አትፈራም ፥
የቤትዋ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ እጥፍ ፡ ድርብ ፡ የለበሱ ፡ ናቸውና ።
፳፪፤ ለራስዋም ፡ ግብረ ፡ መርፌ ፡ ስጋጃ ፡ ትሠራለች ፤
ጥሩ ፡ በፍታና ፡ ቀይ ፡ ግምጃ ፡ ትለብሳለች ።
፳፫፤ ባልዋ ፡ በአገር ፡ ሽማግሌዎች ፡ መካከል ፡ በሸንጎ ፡ በተቀመጠ ፡ ጊዜ ፡
በበር ፡ የታወቀ ፡ ይሆናል ።
፳፬፤ የበፍታ ፡ ቀሚስ ፡ እየሠራች ፡ ትሸጣለች ፥
ለነጋዴም ፡ ድግ ፡ ትሸጣለች ።
፳፭፤ ብርታትና ፡ ክብሬታ ፡ ልብስዋ ፡ ነው ፤
በኋላም ፡ ዘመን ፡ ላይ ፡ ትስቃለች ።
፳፮፤ አፍዋን ፡ በጥበብ ፡ ትከፍታለች ፤
የርኅራኄም ፡ ሕግ ፡ በምላስዋ ፡ አለ ።
፳፯፤ የቤትዋን ፡ ሰዎች ፡ አካሄድ ፡ በደኅና ፡ ትመለከታለች ፥
የሀኬትንም ፡ እንጀራ ፡ አትበላም ።
፳፰፤ ልጆችዋ ፡ ይነሣሉ ፥ ምስጋናዋንም ፡ ይናገራሉ ፤
ባልዋ ፡ ደግሞ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ያመሰግናታል ፡—
፳፱፤ መልካም ፡ ያደረጉ ፡ ብዙ ፡ ሴቶች ፡ አሉ ፥
አንቺ ፡ ግን ፡ ከሁሉ ፡ ትበልጫለሽ ።
፴፤ ውበት ፡ ሐሰት ፡ ነው ፥ ደም ፡ ግባትም ፡ ከንቱ ፡ ነው ፤
እግዚአብሔርን ፡ የምትፈራ ፡ ሴት ፡ ግን ፡ እርስዋ ፡ ትመሰገናለች ።
፴፩፤ ከእጅዋ ፡ ፍሬ ፡ ስጡአት ፥
ሥራዎችዋም ፡ በሸንጎ ፡ ያመስግኑአት ።

# መጽሐፈ ፡ መክብብ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ በኢየሩሳሌም ፡ የነገሠ ፡ የሰባኪው ፡ የዳዊት ፡
ልጅ ፡ ቃል ።
፪፤ ሰባኪው ፡— ከንቱ ፥ ከንቱ ፥ የከንቱ ፡ ከንቱ ፤
፫፤ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ ይላል ። ከፀሐይ ፡ በታች ፡
በሚደክምበት ፡ ድካም ፡ ሁሉ ፡ የሰው ፡ ትርፉ ፡
፬፤ ምንድር ፡ ነው ? ትውልድ ፡ ይሄዳል ፥ ትውል
ድም ፡ ይመጣል ፤ ምድር ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ነው ።
፭፤ ፀሐይ ፡ ትወጣለች ፥ ፀሐይም ፡ ትገባለች ፥ ወደም
፮፤ ትወጣበትም ፡ ስፍራ ፡ ትቸኵላለች ። ነፋስ ፡ ወደ ፡
ደቡብ ፡ ይሄዳል ፥ ወደ ፡ ሰሜንም ፡ ይዞራል ፤
ዘወትር ፡ በዙረቱ ፡ ይዞራል ፥ ነፋስም ፡ በዙረቱ ፡
፯፤ ደግሞ ፡ ይመለሳል ። ፈሳሾች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡
ባሕር ፡ ይሄዳሉ ፥ ባሕሩ ፡ ግን ፡ አይሞላም ፤
ፈሳሾች ፡ ወደሚሄዱበት ፡ ስፍራ ፡ እንደ ፡ ገና ፡
፰፤ ወደዚያ ፡ ይመለሳሉ ። ነገር ፡ ሁሉ ፡ ያደክ
ማል ፤ ሰው ፡ ይናገረው ፡ ዘንድ ፡ አይችልም ፤
ዓይን ፡ ከማየት ፡ አይጠግብም ፥ ጆሮም ፡ ከመ
ስማት ፡ አይሞላም ።
፱፤ የሆነው ፡ ነገር ፡ እርሱ ፡ የሚሆን ፡ ነው ፥ የተ
ደረገውም ፡ ነገር ፡ እርሱ ፡ የሚደረግ ፡ ነው ፤ ከፀሐ
፲፤ ይም ፡ በታች ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ የለም ። ማንም ፡—
እነሆ ፥ ይህ ፡ ነገር ፡ አዲስ ፡ ነው ፡ ይል ፡ ዘንድ ፡
ይችላልን ? እርሱ ፡ ከእኛ ፡ በፊት ፡ በነበሩት ፡
፲፩፤ ዘመናት ፡ ተደርጎአል ። ለፊተኞቹ ፡ ነገሮች ፡
መታሰቢያ ፡ የላቸውም ፤ ለኋለኞቹም ፡ ነገሮች ፡
ከእነርሱ ፡ በኋላ ፡ በሚነሡት ፡ ሰዎች ፡ ዘንድ ፡
መታሰቢያ ፡ አይገኝላቸውም ።
፲፪፤ እኔ ፡ ሰባኪው ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ በኢየሩሳ
፲፫፤ ሌም ፡ ንጉሥ ፡ ነበርሁ ። ከሰማይም ፡ በታች ፡
የተደረገውን ፡ ሁሉ ፡ በጥበብ ፡ እፈልግና ፡ እመ
ረምር ፡ ዘንድ ፡ ልቤን ፡ አተጋሁ ፤ እግዚአብ
ሔር ፡ ይደክሙበት ፡ ዘንድ ፡ ይህችን ፡ ለሰው ፡
፲፬፤ ልጆች ፡ የሰጠ ፡ ክፉ ፡ ጥረት ፡ ናት ። ከፀሐይ ፡
በታች ፡ የተሠራውን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አየሁ ፤
እነሆም ፥ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ነው ፥ ነፋስንም ፡ እንደ ፡
፲፭፤ መከተል ፡ ነው ። ጠማማ ፡ ይቀና ፡ ዘንድ ፡ አይች
ልም ፤ ጐደሎም ፡ ይቈጠር ፡ ዘንድ ፡ አይች
ልም ።
፲፮፤ እኔ ፡ በልቤ ፡— እነሆ ፥ ከእኔ ፡ አስቀድመው ፡
በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ ከነበሩት ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡
ጥበብን ፡ አብዝቼ ፡ ጨመርሁ ፤ ልቤም ፡ ብዙ ፡
ጥበብንና ፡ እውቀትን ፡ ተመለከተ ፡ ብዬ ፡ ተና
፲፯፤ ገርሁ ። ጥበብንና ፡ ዕብደትን ፡ ሞኝነትንም ፡
አውቅ ፡ ዘንድ ፡ ልቤን ፡ ሰጠሁ ፤ ይህም ፡ ደግሞ ፡
ነፋስን ፡ እንደ ፡ መከተል ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስተዋ
፲፰፤ ልሁ ። በጥበብ ፡ መብዛት ፡ ትካዜ ፡ ይበዛልና ፤
እውቀትንም ፡ የሚጨምር ፡ ኀዘንን ፡ ይጨም
ራልና ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፤ እኔ ፡ በልቤ ፡— ና ፡ በደስታም ፡ እፈትንሃ
ለሁ ፥ መልካምንም ፡ ቅመስ ፡ አልሁ ፤ ይህም ፡
፪፤ ደግሞ ፡ እነሆ ፡ ከንቱ ፡ ነበረ ። ሳቅን ፡— ዕብድ ፡
ነህ ፤ ደስታንም ፡— ምን ፡ ታደርጋለህ ? አልሁት ።
፫፤ የሰው ፡ ልጆች ፡ በሕይወታቸው ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡
ከፀሐይ ፡ በታች ፡ ሊሠሩት ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ምን ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ እስካይ ፡ ድረስ ፡ ልቤ ፡ በጥበብ ፡
እየመራኝ ፥ ሰውነቴን ፡ በወይን ፡ ጠጅ ፡ ደስ ፡ ለማ
ሰኘት ፡ ስንፍናንም ፡ ለመያዝ ፡ በልቤ ፡ መረመ
፬፤ ርሁ ። ትልቅ ፡ ሥራን ፡ ሠራሁ ፥ ቤቶችንም ፡ አደረ
፭፤ ግሁ ፥ ወይንም ፡ ተከልሁ ፤ አትክልትንና ፡ ገነ
ትን ፡ አደረግሁ ፥ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ፍሬ ፡ ያለባቸው
፮፤ ንም ፡ ዛፎች ፡ ተከልሁባቸው ፤ በዱር ፡ የተተከ
ሉትን ፡ ዛፎች ፡ አጠጣበት ፡ ዘንድ ፡ የውኃ ፡
፯፤ ማጠራቀሚያ ፡ አደረግሁ ። ወንዶችንና ፡ ሴቶ
ችን ፡ ባሪያዎች ፡ ገዛሁ ፥ የቤት ፡ ውልድ ፡ ባሪ
ያዎችም ፡ ነበሩኝ ፤ ከእኔ ፡ አስቀድመው ፡ በኢ
የሩሳሌም ፡ ከነበሩት ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ብዙ ፡ ከብ
፰፤ ቶችና ፡ መንጋዎች ፡ ነበሩኝ ። ብርንና ፡ ወር
ቅን ፡ የከበረውንም ፡ የነገሥታትና ፡ የአውራጆ
ችን ፡ መዝገብ ፡ ሰበሰብሁ ፤ አዝማሪዎችንና ፡
አርሆዎችን ፡ የሰዎች ፡ ልጆችንም ፡ ተድላ ፡ እጅግ
፱፤ የበዙ ፡ ሴቶችንም ፡ አከማቸሁ ። ታላቅም ፡
ሆንሁ ፥ ከእኔም ፡ አስቀድመው ፡ በኢየሩሳ
ሌም ፡ ከነበሩት ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ከበርሁ ፤ ደግ
ሞም ፡ ጥበቤ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ጸንታ ፡ ቀረች ።
፲፤ ዓይኖቼንም ፡ ከፈለጉት ፡ ሁሉ ፡ አልከለከልኋ
ቸውም ፤ ልቤም ፡ በድካሜ ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ይለው ፡
ነበርና ፡ ልቤን ፡ ከደስታ ፡ ሁሉ ፡ አላራቅሁትም ፤
ከድካሜም ፡ ሁሉ ፡ ይህ ፡ እድል ፡ ፈንታዬ ፡ ሆነ ።
፲፩፤ እጆ ፡ የሠራቻትን ፡ ሥራዬን ፡ ሁሉ ፡ የደከም
ሁበትንም ፡ ድካሜን ፡ ሁሉ ፡ ተመለከትሁ ፤
እነሆ ፥ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ነፋስንም ፡ እንደ ፡ መከ
ተል ፡ ነበረ ፥ ከፀሐይ ፡ በታችም ፡ ትርፍ ፡ አል
ነበረም ።
፲፪፤ እኔም ፡ ጥበብን ፡ ዕብደትንና ፡ ስንፍናን ፡ አይ ፡
ዘንድ ፡ ተመለከትሁ ፤ በፊት ፡ ከተደረገው ፡
በቀር ፥ ከንጉሥ ፡ በኋላ ፡ የሚመጣው ፡ ሰው ፡
፲፫፤ ምን ፡ ያደርጋል ? እኔም ፡ ብርሃን ፡ ከጨለማ ፡
እንደሚበልጥ ፡ እንዲሁ ፡ ጥበብ ፡ ከስንፍና ፡
፲፬፤ እንዲበልጥ ፡ አየሁ ። የጠቢብ ፡ ዓይኖች ፡ በራሱ ፡
ላይ ፡ ናቸው ፥ ሰነፍ ፡ ግን ፡ በጨለማ ፡ ይሄዳል ፤
ደግሞ ፡ ለሁለቱ ፡ መጨረሻቸው ፡ አንድ ፡ እንደ ፡
፲፭፤ ሆነ ፡ አስተዋልሁ ። እኔም ፡ በልቤ ፡— ለሰነፍ ፡
የሚደርሰው ፡ ለእኔም ፡ ይደርሳል ፤ ለምን ፡
እጅግ ፡ ጠቢብ ፡ ሆንሁ ? አልሁ ። የዚያን ፡
ጊዜም ፡ በልቤ ፡— ይህ ፡ ደግሞ ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡
፲፮፤ አልሁ ። በሚመጣው ፡ ዘመን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡

የተረሳ፡ ይሆናልና፡ ለዘላለም፡ የሚሆን፡ የጠቢብና፡ የሰነፍ፡ መታሰቢያ፡ አይገኝም ። አዬ፡ ጉድ! ጠቢብ፡ ከሰነፍ፡ ጋር፡ እንዴት፡ ይሞታል! ፲፯ ከፀሐይም፡ በታች፡ የተሠራው፡ ሥራ፡ ሁሉ፡ ከብዶብኛልና፡ ሕይወትን፡ ጠላሁ፤ ሁሉም፡ ከንቱ፡ ነፋስንም፡ እንደ፡ መከተል፡ ነው ።

፲፰ ከእኔ፡ በኋላ፡ ለሚመጣው፡ ሰው፡ እተወዋለሁና፡ ከፀሐይ፡ በታች፡ የደከምሁበትን፡ ሁሉ፡ ጠላሁት ። ፲፱ ጠቢብ፡ ወይም፡ ሰነፍ፡ እንዲሆን፡ የሚያውቅ፡ ሰው፡ ማን፡ ነው? ከፀሐይ፡ በታች፡ በደከምሁበትና፡ ጠቢብ፡ በሆንሁበት፡ በድካሜ፡ ሁሉ፡ ላይ፡ ጌታ፡ ይሆንበታል፤ ይህም፡ ደግሞ፡ ከንቱ፡ ነው ። ፳ እኔም፡ ተመልሼ፡ ልቤን፡ ከፀሐይ፡ በታች፡ በደከምሁበት፡ ድካም፡ ሁሉ፡ ተስፋ፡ አስቈረጥሁት ። ፳፩ ሰው፡ በጥበብና፡ በእውቀት፡ በብልሃትም፡ ከደከመ፡ በኋላ፡ ለሌላ፡ ላልደከመበት፡ ሰው፡ ያወርሰዋልና፤ ይህም፡ ደግሞ፡ ከንቱ፡ ትልቅም፡ መከራ፡ ነው ። ፳፪ ከፀሐይ፡ በታች፡ በደከመበት፡ ድካም፡ ሁሉና፡ በልቡ፡ አሳብ፡ የሰው፡ ጥቅም፡ ምንድር፡ ነው? ፳፫ ዘመኑ፡ ሁሉ፡ ኀዘን፥ ጥረትም፡ ትካዜ፡ ነው፤ ልቡም፡ በሌሊት፡ አይተኛም፤ ይህም፡ ደግሞ፡ ከንቱ፡ ነው ።

፳፬ ለሰው፡ ከሚበላና፡ ከሚጠጣ፡ በድካሙም፡ ደስ፡ ከሚለው፡ በቀር፡ የሚሻለው፡ ነገር፡ የለም፤ ይህም፡ ደግሞ፡ ከእግዚአብሔር፡ እጅ፡ እንደ፡ ተሰጠ፡ አየሁ ። ፳፭ ያለ፡ እርሱ፡ ፈቃድ፡ የበላ፡ ደስ፡ ብሎትም፡ ተድላን፡ የቀመሰ፡ ማን፡ ነው? ፳፮ እርሱም፡ ደስ፡ ለሚያሰኘው፡ ሰው፡ ጥበብንና፡ እውቀትን፡ ደስታንም፡ ይሰጠዋል፤ ለኃጢአተኛ፡ ግን፡ እግዚአብሔርን፡ ደስ፡ ለሚያሰኘው፡ ሰው፡ ይሰጥ፡ ዘንድ፡ እንዲሰበስብና፡ እንዲያከማች፡ ጥረትን፡ ይሰጠዋል ። ይህም፡ ደግሞ፡ ከንቱ፡ ነፋስንም፡ እንደ፡ መከተል፡ ነው ።

## ምዕራፍ፡ ፫ ።

፩ ለሁሉ፡ ዘመን፡ አለው፥ ከሰማይ፡ በታችም፡ ለሆነ፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ጊዜ፡ አለው ። ፪ ለመወለድ፡ ጊዜ፡ አለው፥ ለመሞትም፡ ጊዜ፡ አለው፤ ለመትከል፡ ጊዜ፡ አለው፥ የተተከለውንም፡ ለመንቀል፡ ጊዜ፡ አለው፤ ፫ ለመግደል፡ ጊዜ፡ አለው፥ ለመፈወስም፡ ጊዜ፡ አለው፤ ለማፍረስ፡ ጊዜ፡ አለው፥ ለመሥራትም፡ ጊዜ፡ አለው፤ ፬ ለማልቀስ፡ ጊዜ፡ አለው፥ ለመሳቅም፡ ጊዜ፡ አለው፤ ዋይ፡ ለማለት፡ ጊዜ፡ አለው፥ ለመዝፈንም፡ ጊዜ፡ አለው፤ ፭ ድንጋይን፡ ለመጣል፡ ጊዜ፡ አለው፥ ድንጋይንም፡ ለመሰብሰብ፡ ጊዜ፡ አለው፤ ለመተቃቀፍ፡ ጊዜ፡ አለው፥ ከመተቃቀፍም፡ ለመራቅ፡ ጊዜ፡ አለው፤ ፮ ለመፈለግ፡ ጊዜ፡ አለው፥ ለማጥፋትም፡ ጊዜ፡ አለው፤ ለመጠበቅ፡ ጊዜ፡ አለው፥ ለመጣልም፡ ጊዜ፡ አለው፤ ፯ ለመቅደድ፡ ጊዜ፡ አለው፥ ለመስፋትም፡ ጊዜ፡ አለው፤ ዝም፡ ለማለት፡ ጊዜ፡ አለው፥ ለመናገርም፡ ጊዜ፡ አለው፤ ፰ ለመውደድ፡ ጊዜ፡ አለው፥ ለመጥላትም፡ ጊዜ፡ አለው፤ ለጦርነት፡ ጊዜ፡ አለው፥ ለሰላምም፡ ጊዜ፡ አለው ። ፱ ለሠራተኛ፡ የድካሙ፡ ትርፍ፡ ምንድር፡ ነው?

፲ እግዚአብሔር፡ ለሰው፡ ልጆች፡ ይደክሙበት፡ ዘንድ፡ የሰጣቸውን፡ ጥረት፡ አይቻለሁ ። ፲፩ ነገርን፡ ሁሉ፡ በጊዜው፡ ውብ፡ አድርጎ፡ ሠራው፤ እግዚአብሔርም፡ ከጥንት፡ ጀምሮ፡ እስከ፡ ፍጻሜ፡ ድረስ፡ የሠራውን፡ ሥራ፡ ሰው፡ መርምሮ፡ እንዳያገኝ፡ ዘላለምነትን፡ በልቡ፡ ሰጠው ። ፲፪ ሰው፡ ደስ፡ ከሚለውና፡ በሕይወቱ፡ ሳለ፡ መልካምን፡ ነገር፡ ከሚያደርግ፡ በቀር፡ መልካም፡ ነገር፡ እንደሌለ፡ አወቅሁ ። ፲፫ ደግሞም፡ ሰው፡ ሁሉ፡ ይበላና፡ ይጠጣ፡ ዘንድ፡ በድካሙም፡ ሁሉ፡ ደስ፡ ይለው፡ ዘንድ፡ የእግዚአብሔር፡ ስጦታ፡ ነው ። ፲፬ እግዚአብሔር፡ ያደረገው፡ ሁሉ፡ ለዘላለም፡ እንዲኖር፡ አወቅሁ፤ ሊጨመርበት፡ ወይም፡ ከእርሱ፡ ሊጐድል፡ አይቻልም፤ እግዚአብሔርም፡ በፊቱ፡ ይፈሩ፡ ዘንድ፡ አደረገ ። ፲፭ አሁን፡ ያለው፡ በፊት፡ ነበረ፥ የሚሆነውም፡ በፊት፡ ሆኖ፡ ነበር፤ እግዚአብሔርም፡ ያለፈውን፡ መልሶ፡ ይሻዋል ።

፲፮ ደግሞም፡ ከፀሐይ፡ በታች፡ በፍርድ፡ ስፍራ፡ ኃጢአት፥ በጽድቅም፡ ስፍራ፡ ኃጢአት፡ እንዳለ፡ አየሁ ። ፲፯ እኔም፡ በልቤ፦ በዚያ፡ ለነገር፡ ሁሉና፡ ለሥራ፡ ሁሉ፡ ጊዜ፡ አለውና፡ በጻድቅና፡ በኃጢአተኛ፡ ላይ፡ እግዚአብሔር፡ ይፈርዳል፡ አልሁ ። ፲፰ እኔ፡ በልቤ፡ ስለ፡ ሰው፡ ልጆች፦ እንደ፡ እንስሳ፡ መሆናቸውን፡ እንዲያዩ፡ እግዚአብሔር፡ ይፈትናቸዋል፡ አልሁ ። ፲፱ የሰው፡ ልጆችና፡ የእንስሳ፡ እድል፡ ፈንታ፡ አንድ፡ ነው፤ ድርሻቸውም፡ ትክክል፡ ነው፤ አንዱ፡ እንደሚሞት፡ ሌላውም፡ እንዲሁ፡ ይሞታል፤ የሁሉም፡ እስትንፋስ፡ አንድ፡ ነው፤ ሁሉም፡ ከንቱ፡ ነውና፡ ሰው፡ ከእንስሳ፡ ብልጫ፡ የለውም ። ፳ ሁሉ፡ ወደ፡ አንድ፡ ቦታ፡ ይሄዳል፤ ሁሉ፡ ከአፈር፡ ነው፡ ሁሉም፡ ወደ፡ አፈር፡ ይመለሳል ። ፳፩ የሰው፡ ልጆች፡ ነፍስ፡ ወደ፡ ላይ፡ እንደምትወጣ፡ የእንስሳም፡ ነፍስ፡ ወደ፡ ታች፡ ወደ፡ ምድር፡ እንደምትወርድ፡ የሚያውቅ፡ ማን፡ ነው? ፳፪ ያም፡ እድል፡ ፈንታው፡ ነውና፡ ሰው፡ በሥራው፡ ደስ፡ ከሚለው፡ በቀር፡ ሌላ፡ መልካም፡ ነገር፡ እንደሌለው፡ አየሁ፤ ከእርሱ፡ በኋላስ፡ የሚሆነውን፡ ያይ፡ ዘንድ፡ የሚያመጣው፡ ማን፡ ነው?

## ምዕራፍ፡ ፬ ።

፩ እኔም፡ ተመለስሁ፥ ከፀሐይ፡ በታችም፡ የሚደረገውን፡ ግፍ፡ ሁሉ፡ አየሁ፤ እነሆም፥ የተገፉት፡ ሰዎች፡ እንባ፡ ነበረ፤ የሚያጽናናቸውም፡ አልነበረም፤ በሚገፉአቸውም፡ እጅ፡ ኃይል፡ ነበረ፥ እነርሱን፡ ግን፡ የሚያጽናናቸው፡ አልነበረም ። ፪ እኔም፡ እስከ፡ ዛሬ፡ በሕይወት፡ ካሉት፡

ይልቅ ፡ በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ የሞቱትን ፡ አመሰገ
፫፤ ንሁ ፤ ከእነዚህም ፡ ከሁለቱ ፡ ይልቅ ፡ ገና ፡ ያል
ተወለደው ፡ ከፀሐይም ፡ በታች ፡ የሚደረገውን ፡
ግፍ ፡ ያላየው ፡ ይሻላል ።
፬፤ ደግሞም ፡ የሰውን ፡ ድካምና ፡ የብልሃት ፡
ሥራውን ፡ ሁሉ ፡ ተመለከትሁ ፥ በባልንጀራ
ውም ፡ ዘንድ ፡ ቅንዓት ፡ እንዲያስነሣ ፡ አየሁ ፤
ይህም ፡ ደግሞ ፡ ከንቱ ፡ ነፋስንም ፡ እንደ ፡ መከ
፭፤ ተል ፡ ነው ። ሰነፍ ፡ እጆቹን ፡ ከርትሞ ፡ ይቀ
፮፤ መጣል ፤ የገዛ ፡ ሥጋውንም ፡ ይበላል ። በድካ
ምና ፡ ነፋስን ፡ በመከተል ፡ ከሁለት ፡ እጅ ፡ሙሉ ፡
ይልቅ ፡ አንድ ፡ እጅ ፡ ሙሉ ፡ በዕረፍት ፡ ይሻላል ።
፯፤ እኔም ፡ ተመለስሁ ፥ ከፀሐይ ፡ በታችም ፡ ከን
፰፤ ቱን ፡ ነገር ፡ አየሁ ። አንድ ፡ ሰው ፡ ብቻውን ፡
አለ ፥ ሁለተኛም ፡ የለውም ፤ ልጅም ፡ ሆነ ፡ ወን
ድም ፡ የለውም ፤ ለድካሙ ፡ ግን ፡ መጨረሻ ፡
የለውም ፥ ዓይኖቹም ፡ ከባለጠግነት ፡ አይጠግ
ቡም ። ለማን ፡ እደክማለሁ ፥ ሰውነቴንስ ፡ መል
ካሙን ፡ ነገር ፡ ለምን ፡ እነፍጋታለሁ ? ይላል ።
ይህም ፡ ደግሞ ፡ ከንቱ ፡ ነገር ፡ ክፉም ፡ ጥረት ፡
፱፤ ነው ። ድካማቸው ፡ መልካም ፡ ዋጋ ፡ አለውና ፡
አንድ ፡ ብቻ ፡ ከመሆን ፡ ሁለት ፡ መሆን ፡ ይሻ
፲፤ ላል ። ቢወድቁ ፡ አንዱ ፡ ሁለተኛውን ፡ ያነሣዋ
ልና ፤ አንዱ ፡ ብቻውን ፡ ሆኖ ፡ በወደቀ ፡ ጊዜ ፡
ግን ፡ የሚያነሣው ፡ ሁለተኛ ፡ የለውምና ፡ ወዮ
፲፩፤ ለት ። ሁለቱም ፡ በአንድነት ፡ ቢተኙ ፡ ይሞቃ
ቸዋል ፤ አንድ ፡ ብቻውን ፡ ግን ፡ እንዴት ፡ ይሞ
፲፪፤ ቀዋል ? አንዱም ፡ አንዱን ፡ ቢያሸንፍ ፡ ሁለቱ ፡
በፊቱ ፡ ይቆማሉ ፤ በሦስትም ፡ የተገመደ ፡ ገመድ ፡
ፈጥኖ ፡ አይበጠስም ።
፲፫፤ ድሀና ፡ ጠቢብ ፡ ብላቴና ፡ ተግሣጽን ፡ መቀ
በል ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ከማያውቅ ፡ ከሰነፍ ፡
፲፬፤ ሽማግሌ ፡ ንጉሥ ፡ ይሻላል ። ምንም ፡ በመን
ግሥቱ ፡ አገር ፡ ደግሞ ፡ ችግረኛ ፡ ሆኖ ፡ ቢወ
ለድ ፥ ከግዞቱ ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ መንግሥት ፡ ወጥ
፲፭፤ ቶአልና ። ከፀሐይ ፡ በታች ፡ የሚሄዱትን ፡
ሕያዋን ፡ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ከሚነሣው ፡
፲፮፤ ከሌላው ፡ ጐበዝ ፡ ጋር ፡ ሆነው ፡ አየሁ ። ከእ
ርሱ ፡ በፊት ፡ የተገዙለት ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ አይ
ቈጠሩም ፤ በኋላ ፡ የሚመጡት ፡ ግን ፡ በእርሱ ፡
ደስ ፡ አይላቸውም ። ይህም ፡ ደግሞ ፡ ከንቱ ፡
ነፋስንም ፡ እንደ ፡ መከተል ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩፤ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በገባህ ፡ ጊዜ ፡
እግርህን ፡ ጠብቅ ፤ ለመስማት ፡ መቅረብ ፡ ከሰነ
ፎች ፡ መሥዋዕት ፡ ይበልጣልና ፤ እነርሱም ፡
፪፤ ክፉ ፡ እንዲያደርጉ ፡ አያውቁምና ። እግዚአ
ብሔር ፡ በሰማይ ፥ አንተም ፡ በምድር ፡ ነህና ፡
በአፍህ ፡ አትፍጠን ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡
ቃልን ፡ ይናገር ፡ ዘንድ ፡ ልብህ ፡ አይቸኵል ፤
፫፤ ስለዚህም ፡ ቃልህ ፡ጥቂት ፡ ትሁን ። ሕልም ፡
በሥራ ፡ ብዛት ፡ ይታያል ፤ እንዲሁም ፡ የሰነፍ ፡
፬፤ ድምፅ ፡ በቃሉ ፡ ብዛት ፡ ይሰማል ። ሰነፎች ፡
ደስ ፡ አያሰኙትምና ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስእለት ፡
በተሳልህ ፡ ጊዜ ፡ ትፈጽመው ፡ ዘንድ ፡ አትዘ
፭፤ ግይ ፤ የተሳልኸውን ፡ ፈጽመው ። ተስለህ ፡
የማትፈጽም ፡ ብትሆን ፡ ባትሳል ፡ ይሻላል ።
፮፤ ሥጋህን ፡ በኃጢአት ፡ እንዳያስተው ፡ ለአፍህ ፡
አርነት ፡ አትስጥ ፥ በመልአክም ፡ ፊት ፡— ስሕ
ተት ፡ ነበረ ፡ አትበል ፤ እግዚአብሔር ፡ በቃ
ልህ ፡ ይቈጣ ፡ ዘንድ ፡ የእጅህንም ፡ ሥራ ፡
፯፤ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትሻለህ ? ብዙ ፡ ሕልም ፡
ባለበት ፡ ዘንድ ፥ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ ብዙ ፡
ቃል ፡ ባለበት ፡ ስፍራ ፡ በዚያ ፡ ብዙ ፡ ከንቱ ፡
ነገር ፡ አለ ፤ አንተ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡
ፍራ ።
፰፤ ከፍ ፡ ካለው ፡ በላይ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ይመለከታ
ልና ፥ ከእነርሱም ፡ በላይ ፡ ደግሞ ፡ ሌሎች ፡
ከፍ ፡ ይላሉና ፡ በአገሩ ፡ ድሆች ፡ ሲገፉ ፥ ፍር
ድና ፡ ጽድቅም ፡ ሲነጠቅ ፡ ባየህ ፡ ጊዜ ፡ በዚህ ፡
፱፤ ነገር ፡ አታድንቅ ። በጠቅላላው ፡ ግን ፡ የአገሩ ፡
ጥቅም ፡ እርሻን ፡ የሚወድድ ፡ ንጉሥ ፡ ቢኖር ፡
ነው ።
፲፤ ብርን ፡ የሚወድድ ፡ ሰው ፡ ብርን ፡ አይጠግ
ብም ፤ ባለጠግነትንም ፡ የሚወድድ ፡ ትርፉን ፡
አይጠግብም ፤ ይህም ፡ ደግሞ ፡ ከንቱ ፡ ነው ።
፲፩፤ ሀብት ፡ ሲበዛ ፡ የሚበሉት ፡ ይበዛሉ ፤ ሀብቱን ፡
በዓይኑ ፡ ብቻ ፡ ከማየት ፡ በቀር ፡ ለባለቤቱ ፡ ምን ፡
፲፪፤ ይጠቅመዋል ? እጅግ ፡ ወይም ፡ ጥቂት ፡ ቢበላ ፡
የሠራተኛ ፡ እንቅልፍ ፡ ጣፋጭ ፡ ነው ፤ የባለ
ጠጋ ፡ ጥጋብ ፡ ግን ፡ እንቅልፍን ፡ ይከለክለ
ዋል ።
፲፫፤ ከፀሐይ ፡ በታች ፡ የሚያሳዝን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡
አየሁ ፤ ለመከራው ፡ በባለቤቱ ፡ ዘንድ ፡ የተቈ
፲፬፤ ጠበች ፡ ባለጠግነት ፡ ናት ። ያችም ፡ ባለጠግ
ነት ፡ በክፉ ፡ ነገር ፡ ትጠፋለች ፤ ልጅንም ፡ ቢወ
፲፭፤ ልድ ፡ በእጁ ፡ ምንም ፡ የለውም ። ከእናቱ ፡ ሆድ ፡
ራቁቱን ፡ እንደ ፡ ወጣ ፡ እንዲሁ ፡ እንደ ፡ መጣው ፡
ይመለሳል ፤ ከጥረቱም ፡ በእጁ ፡ ሊወስድ ፡ የሚ
፲፮፤ ችለውን ፡ ምንም ፡ አያገኝም ። ይህም ፡ ደግሞ ፡
የሚያሳዝን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ነው ፤ እንደ ፡ መጣ ፡
እንዲሁ ፡ ይሄዳል ፤ ድካሙም ፡ ለነፋስ ፡ ከሆነ ፡
፲፯፤ ጥቅሙ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ዘመኑን ፡ ሁሉ ፡ በጨ
ለማ ፡ በኀዘን ፡ በብስጭት ፡ በደዌና ፡ በቍጣ ፡
ነው ።
፲፰፤ እነሆ ፥ እኔ ፡ ያየሁት ፡ መልካምና ፡ የተዋበ ፡
ነገር ፡ ሰው ፡ እግዚአብሔር ፡ በሰጠው ፡ በሕይ
ወቱ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ይበላና ፡ ይጠጣ ፡ ዘንድ ፥
ከፀሐይ ፡ በታችም ፡ በሚደክምበት ፡ ድካም ፡
ሁሉ ፡ ደስ ፡ ይለው ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤ ይህ ፡ እድል ፡
፲፱፤ ፈንታው ፡ ነውና ። እግዚአብሔር ፡ ለሰው ፡ ሁሉ ፡
ባለጠግነትንና ፡ ሀብትን ፡ መስጠቱ ፥ ከእርስ
ዋም ፡ ይበላና ፡ እድል ፡ ፈንታውን ፡ ይወስድ ፡
ዘንድ ፡ በድካሙም ፡ ደስ ፡ ይለው ፡ ዘንድ ፡ ማሠ
ልጠኑ ፤ ይህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ስጦታ ፡ ነው ።
፳፤ እግዚአብሔር ፡ በልቡ ፡ ደስታን ፡ ስለ ፡ ሰጠው ፡
እርሱ ፡ የሕይወቱን ፡ ዘመን ፡ እጅግ ፡ አያስብም ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩፤ ከፀሐይ ፡ በታች ፡ ያየሁት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አለ ፥
እርሱም ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡ የከበደ ፡ ነው ።
፪፤ እግዚአብሔር ፡ ለሰው ፡ ሀብትንና ፡ ጥሪትን ፡
ክብርንም ፡ ሰጠው ፥ ከወደደውም ፡ ሁሉ ፡ ለነ
ፍሱ ፡ አልጐደለውም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡
ይበላዋል ፡ እንጂ ፡ ከእርሱ ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ አላሠለጠነውም ፤ ይህም ፡ ከንቱና ፡
፫፤ ክፉ ፡ ደዌ ፡ ነው ። ሰው ፡ መቶ ፡ ልጆች ፡ ቢወ
ልድ ፡ እጅግ ፡ ዘመንም ፡ በሕይወት ፡ ቢኖር ፡
ዕድሜውም ፡ እጅግ ፡ ዓመት ፡ ቢሆን ፥ ነፍሱም ፡
መልካምን ፡ ባትጠግብ ፡ መቃብርንም ፡ ባያገኝ ፥
እኔ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡— ከእርሱ ፡ ይልቅ ፡ ጭንጋፍ ፡
፬፤ ይሻላል ፡ አልሁ ። በከንቱ ፡ መጥቶአል ፡ በጨ
ለማም ፡ ይሄዳል ፡ ስሙም ፡ በጨለማ ፡ ይሸፈ
፭፤ ናል ፤ ደግሞም ፡ ፀሐይን ፡ አላየውም ፡ አላወቀ
ውምም ፤ ለዚህም ፡ ከዚያ ፡ ይልቅ ፡ ዕረፍት ፡
፮፤ አለው ። ሺህ ፡ ዓመት ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ በሕይ
ወት ፡ ቢኖር ፡ መልካምንም ፡ ባያይ ፥ ሁሉ ፡
ወደ ፡ አንድ ፡ ስፍራ ፡ የሚሄድ ፡ አይደለምን ?
፯፤ የሰው ፡ ድካም ፡ ሁሉ ፡ ለአፉ ፡ ነው ፥ ነፍሱ ፡
፰፤ ግን ፡ አትጠግብም ። ከሰነፍ ፡ ይልቅ ፡ ለጥበ
በኛ ፡ ጥቅም ፡ ምንድር ፡ ነው ? በሕያዋን ፡
ፊትስ ፡ መሄድ ፤ ለሚያውቅ ፡ ለድሀ ፡ ጥቅሙ ፡
፱፤ ምንድር ፡ ነው ? በዓይን ፡ ማየት ፡ በነፍስ ፡ ከመ
ቅበዝበዝ ፡ ይሻላል ፤ ይህም ፡ ደግሞ ፡ ከንቱ ፡
ነፋስንም ፡ እንደ ፡ መከተል ፡ ነው ።
፲፤ የሆነው ፡ ስሙ ፡ አስቀድሞ ፡ ተጠራ ፥ ሰውም ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ ታወቀ ፤ ከእርሱ ፡ ከሚበረታው ፡
፲፩፤ ጋር ፡ ይፋረድ ፡ ዘንድ ፡ አይችልም ። ከንቱን ፡
የሚያበዛ ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ አለና ፡ ለሰው ፡ ጥቅሙ ፡
፲፪፤ ምንድር ፡ ነው ? ሰው ፡ በከንቱ ፡ ወራቱ ፡ ቍጥ
ርና ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ በሚያሳልፈው ፡ ዘመኑ ፡
በሕይወቱ ፡ ሳለ ፡ ለሰው ፡ የሚሻለውን ፡ የሚያ
ውቅ ፡ ማነው ? ወይስ ፡ ለሰው ፡ ከፀሐይ ፡ በታች ፡
ከእርሱ ፡ በኋላ ፡ የሚሆነውን ፡ ማን ፡ ይነግረዋል ?

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩፤ ከመልካም ፡ ሽቱ ፡ መልካም ፡ ስም ፥ ከመወለድ ፡
፪፤ ቀንም ፡ የሞት ፡ ቀን ፡ ይሻላል ። ወደ ፡ ግብዣ ፡
ቤት ፡ ከመሄድ ፡ ወደ ፡ ልቅሶ ፡ ቤት ፡ መሄድ ፡
ይሻላል ፤ እርሱ ፡ የሰው ፡ ሁሉ ፡ ፍጻሜ ፡ ነውና ፥
፫፤ ሕያውም ፡ የሆነ ፡ በልቡ ፡ ያኖረዋልና ። ከሳቅ ፡
ኀዘን ፡ ይሻላል ፥ ከፊት ፡ ኀዘን ፡ የተነሣ ፡ ልብ ፡
፬፤ ደስ ፡ ይሰኛልና ። የጠቢባን ፡ ልብ ፡ በልቅሶ ፡
ቤት ፡ ነው ፤ የሰነፎች ፡ ልብ ፡ ግን ፡ በደስታ ፡
፭፤ ቤት ፡ ነው ። ሰው ፡ የሰነፎችን ፡ ዜማ ፡ ከሚሰማ ፡
ይልቅ ፡ የጠቢባንን ፡ ተግሣጽ ፡ መስማት ፡ ይሻ
፮፤ ለዋል ። ከድስት ፡ በታች ፡ እንደሚቃጠል ፡
እሾህ ፡ ድምፅ ፡ የሰነፍ ፡ ሳቅ ፡ እንዲሁ ፡ ነው ፤
፯፤ ይህም ፡ ደግሞ ፡ ከንቱ ፡ ነው ። ግፍ ፡ ጠቢቡን ፡
፰፤ ያሳብደዋል ፤ ጉቦም ፡ ልቡን ፡ ያጠፋዋል ። የነ
ገር ፡ ፍጻሜ ፡ ከመጀመሪያው ፡ ይሻላል ፤ ታጋ
ሽም ፡ ከትዕቢተኛ ፡ ይሻላል ። በነፍስህ ፡ ለቍጣ ፡ ፱፤
ችኩል ፡ አትሁን ፥ ቍጣ ፡ በሰነፍ ፡ ብብት ፡ ያር
ፋልና ።
፲፤ ከዚህ ፡ ዘመን ፡ ይልቅ ፡ ያለፈው ፡ ዘመን ፡
ለምን ፡ ተሻለ ? ብለህ ፡ አትናገር ፤ የዚህን ፡ ነገር ፡
በጥበብ ፡ አትጠይቅምና ።
፲፩፤ ጥበብ ፡ ከርስት ፡ ጋር ፡ መልካም ፡ ነው ፤ ፀሐ
ይንም ፡ ለሚያዩ ፡ ሰዎች ፡ ትርፍን ፡ ይሰጣል ።
፲፪፤ የጥበብ ፡ ጥላ ፡ እንደ ፡ ገንዘብ ፡ ጥላ ፡ ናትና ፤ የእ
ውቀትም ፡ ብልጫዋ ፡ ጥበብ ፡ ገንዘብ ፡ ላደረ
፲፫፤ ጋት ፡ ሕይወትን ፡ እንድትሰጥ ፡ ነው ። የእግዚአ
ብሔርን ፡ ሥራ ፡ ተመልከት ፤ እርሱ ፡ ጠማማ ፡
፲፬፤ ያደረገውን ፡ ማን ፡ ሊያቀናው ፡ ይችላል ? በመል
ካም ፡ ቀን ፡ ደስ ፡ ይበልህ ፤ በክፉም ፡ ቀን ፡ ተመ
ልከት ፤ ሰው ፡ ከእርሱ ፡ በኋላ ፡ መርምሮ ፡ ምንም ፡
እንዳያገኝ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይህንም ፡ ያንም ፡
እንደዚያ ፡ ሠርቶአል ።
፲፭፤ ጻድቅ ፡ በጽድቁ ፡ ሲጠፋ ፡ ኀጥእም ፡ በክፋቱ ፡
እጅግ ፡ ዘመን ፡ ሲኖር ፥ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡
፲፮፤ በሆነ ፡ ዘመኔ ፡ አየሁ ። እጅግ ፡ ጻድቅ ፡ አትሁን ፥
እጅግ ፡ ጠቢብም ፡ አትሁን ፥ እንዳትጠፋ ።
፲፯፤ እጅግ ፡ ክፉ ፡ አትሁን ፥ አልከኛም ፡ አትሁን ፥
፲፰፤ ጊዜህ ፡ ሳይደርስ ፡ እንዳትሞት ። እግዚአብሔ
ርን ፡ የሚፈራ ፡ ከሁሉ ፡ ይወጣልና ፡ ይህን ፡
ብትይዝ ፡ ከዚያም ፡ ደግሞ ፡ እጅህን ፡ ባታርቅ ፡
መልካም ፡ ነው ።
፲፱፤ በከተማ ፡ ከሚኖሩ ፡ ከአሥር ፡ ገዢዎች ፡
፳፤ ይልቅ ፡ ጥበብ ፡ ጠቢብን ፡ ታበረታለች ። በም
ድር ፡ ላይ ፡ መልካምን ፡ የሚሠራ ፡ ኃጢአትንም ፡
፳፩፤ የማያደርግ ፡ ጻድቅ ፡ አይገኝምና ። ባሪያህ ፡
ሲረግምህ ፡ እንዳትሰማ ፡ በሚጫወቱበት ፡ ቃል ፡
፳፪፤ ሁሉ ፡ ልብህን ፡ አትጣል ፤ አንተ ፡ ደግሞ ፡ ሌሎ
ችን ፡ እንደ ፡ ረገምህ ፡ ልብህ ፡ ያውቃልና ።
፳፫፤ ይህን ፡ ሁሉ ፡ በጥበብ ፡ ፈተንሁ ፤ ጠቢብ ፡
እሆናለሁ ፡ አልሁ ፥ እርስዋ ፡ ግን ፡ ከእኔ ፡ ራቀች ።
፳፬፤ የሆነው ፡ ራቀ ፡ እጅግም ፡ ጠለቀ ፤ መርምሮ ፡
፳፭፤ የሚያገኘውስ ፡ ማን ፡ ነው ? አውቅና ፡ እመረ
ምር ፡ ዘንድ ፥ ጥበብንና ፡ የነገሩን ፡ ሁሉ ፡ መደ
ምደሚያ ፡ እፈልግ ፡ ዘንድ ፥ ኃጢአትም ፡ ስን
ፍና ፥ ስንፍናም ፡ እብደት ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡
፳፮፤ አውቅ ፡ ዘንድ ፡ እኔ ፡ በልቤ ፡ ዞርሁ ። እኔም ፡
ከሞት ፡ ይልቅ ፡ የመረረ ፡ ነገር ፡ መርምሬ ፡ አገ
ኘሁ ፤ እርስዋም ፡ ልብዋ ፡ ወጥመድና ፡ መርበብ ፡
የሆነ ፥ እጆችዋም ፡ እግር ፡ ብረት ፡ የሆኑ ፡ ሴት ፡
ናት ፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ መልካም ፡ የሆነ ፡
ከእርስዋ ፡ ያመልጣል ፥ ኃጢአተኛ ፡ ግን ፡ ይጠ
፳፯፤ መድባታል ። አንዱን ፡ በአንዱ ፡ ላይ ፡ ጨምሬ ፡
ወደ ፡ ነገሩ ፡ ሁሉ ፡ መደምደሚያ ፡ እደርስ ፡ ዘንድ ፥
እነሆ ፥ ይህን ፡ ነገር ፡ አገኘሁ ፡ ይላል ፡ ሰባኪው ፤
፳፰፤ ነፍሴ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ትሻታለች ፥ ነገር ፡
ግን ፡ አላገኘሁም ፤ ከሺህ ፡ ወንዶች ፡ አንድ ፡
አገኘሁ ፥ ከእነዚያ ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ ግን ፡ አን
፳፱፤ ዲት ፡ ሴት ፡ አላገኘሁም ። እግዚአብሔር ፡ ሰዎ
ችን ፡ ቅኖች ፡ አድርጎ ፡ እንደ ፡ ሠራቸው ፥

እነሆ ÷ ይህን ፡ ብቻ ፡ አገኘሁ ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ብልሃትን ፡ ፈለጉ ።

ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ እንደ ፡ ጠቢብ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ማን ፡ ነው ? ነገርንስ ፡ መተርጐም ፡ የሚያውቅ ፡ ማን ፡ ነው ? የሰው ፡ ጥበብ ፡ ፊቱን ፡ ታበራለች ÷ የፊቱንም ፡ ፪ ድፍረት ፡ ትለውጣለች ። እኔ ፡— በእግዚአብሔር ፡ መሐላ ፡ ምክንያት ፡ የንጉሥን ፡ ትእዛዝ ፡ ፫ ጠብቅ ፡ እልሃለሁ ። የወደደውን ፡ ሁሉ ፡ ያደርጋልና ፡ ከፊቱ ፡ ትወገድ ፡ ዘንድ ፡ አትቸኵል ÷ ፬ ክፉንም ፡ በማድረግ ፡ አትጽና ። የንጉሥ ፡ ቃል ፡ ኃይለኛ ፡ ነውና ፤ ይህንስ ፡ ለምን ፡ ታደርጋለህ ? ፭ ማን ፡ ይለዋል ? ትእዛዝን ፡ የሚጠብቅ ፡ ክፉን ፡ ነገር ፡ አያውቅም ፤ የጠቢብም ፡ ልብ ፡ ጊዜንና ፡ ፮ ፍርድን ፡ ያውቃል ። የሰው ፡ መከራ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለነገር ፡ ሁሉ ፡ ጊዜና ፡ ፯ ፍርድ ፡ አለውና ። የሚሆነውንም ፡ አያውቅም ፤ እንዴትስ ፡ እንደሚሆን ፡ የሚነግረው ፡ ማን ፡ ፰ ነው ? መንፈስን ፡ ለማስቀረት ፡ በመንፈስ ፡ ላይ ፡ ሥልጣን ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ የለም ፤ በሞቱም ፡ ቀን ፡ ሥልጣን ፡ የለውም ፤ በሰልፍም ፡ ስንብት ፡ የለም ÷ ኃጢአትም ፡ ሠሪውን ፡ አያድነውም ። ፱ ይህን ፡ ሁሉ ፡ አየሁ ÷ ከፀሐይም ፡ በታች ፡ ወደ ፡ ተደረገው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ልቤን ፡ ሰጠሁ ፤ ሰው ፡ ሰውን ፡ ለመጒዳት ፡ ገዢ ፡ የሚሆንበት ፡ ጊዜ ፡ አለ ።

፲ እንዲሁም ፡ ኃጥአን ፡ ተቀብረው ፡ አየሁ ÷ ወደ ፡ ዕረፍትም ፡ ገቡ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ቅን ፡ አድራጊዎች ፡ ከቅድስት ፡ ስፍራ ፡ ወጡ ÷ በከተማይቱም ፡ ውስጥ ፡ ተረሱ ፤ ይህም ፡ ደግሞ ፡ ከንቱ ፡ ነው ። ፲፩ በክፉ ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ ፈጥኖ ፡ ፍርድ ፡ አይፈረድምና ፡ ስለዚህ ፡ በሰው ፡ ልጆች ፡ ውስጥ ፡ ልባቸው ፡ ክፉን ፡ ለመሥራት ፡ ጠነከረ ። ፲፪ ኃጢአተኛ ፡ መቶ ፡ ጊዜ ፡ ክፉን ፡ ቢሠራ ፡ ዘመኑም ፡ ረጅም ፡ ቢሆን ÷ እግዚአብሔርን ፡ ለሚፈሩት ፡ በፊቱም ፡ ለሚፈሩት ፡ ደኅንነት ፡ እንዲሆን ፡ ፲፫ አውቃለሁ ፤ ለኃጥእ ፡ ግን ፡ ደኅንነት ፡ የለውም ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ አይፈራምና ፡ ዘመኑ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ አትረዝምም ።

፲፬ በምድር ፡ የሚደረግ ፡ ከንቱ ፡ ነገር ፡ አለ ፤ በኃጥአን ፡ የሚደረገው ፡ ሥራ ፡ የሚደርስባቸው ፡ ጻድቃን ፡ አሉ ÷ ለጻድቃንም ፡ የሚደረገው ፡ ሥራ ፡ የሚደርስላቸው ፡ ኃጥአን ፡ አሉ ፤ ፲፭ ይህም ፡ ደግሞ ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ አልሁ ። ከሚበላውና ፡ ከሚጠጣው ፡ ደስም ፡ ከሚለው ፡ በቀር ፡ ለሰው ፡ ከፀሐይ ፡ በታች ፡ ሌላ ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ የለውምና ፡ እኔ ፡ ደስታን ፡ አመሰገንሁ ፤ ከፀሐይም ፡ በታች ፡ ከድካሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሰጠው ፡ በሕይወቱ ፡ ዘመን ፡ ይህ ፡ ደስታው ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይኖራል ።

፲፮ ጥበብን ፡ አውቅ ፡ ዘንድ ፡ በምድር ፡ የሚሆነውንም ፡ ድካም ፡ አይ ፡ ዘንድ ፡ ልቤን ፡ ሰጠሁ ÷ በቀንና ፡ በሌሊት ፡ እንቅልፍን ፡ በዓይኑ ፡ የማያይ ፡ አለና ፤ ፲፯ ከፀሐይም ፡ በታች ፡ የተደረገውን ፡ ሥራ ፡ መርምሮ ፡ ያገኝ ፡ ዘንድ ፡ ለሰው ፡ እንዳይቻለው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አየሁ ። ሰውም ፡ ሊፈልግ ፡ እጅግ ፡ ቢደክም ፡ መርምሮ ፡ አያገኘውም ፤ ደግሞ ፡ ጠቢብ ፡ ሰው ፡— ይህን ፡ አወቅሁ ፡ ቢል ፡ እርሱ ፡ ያገኘው ፡ ዘንድ ፡ አይችልም ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ጻድቃንና ፡ ጠቢባን ፡ ሥራዎቻቸውም ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ሆኑ ÷ ይህን ፡ ሁሉ ፡ እመረምር ፡ ዘንድ ፡ በልቤ ፡ አኖርሁ ፤ ፍቅር ፡ ወይም ፡ ጥል ፡ ቢሆን ፡ ሰው ፡ አያውቅም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ፊታቸው ፡ ነው ። ፪ የጻድቁና ፡ የበደለኛው ÷ የመልካሙና ፡ የክፉው ÷ የንጹሑና ፡ የርኩሱ ÷ መሥዋዕትን ፡ የሚሠዋውና ፡ የማይሠዋው ÷ የሰው ፡ ሁሉ ፡ ድርሻው ፡ አንድ ፡ ነው ፤ እንደ ፡ መልካሙ ፡ ሰው ፡ እንዲሁ ፡ ኃጢአተኛው ÷ እንደ ፡ መሐለኛው ፡ ሰው ፡ እንዲሁ ፡ መሐላን ፡ የሚፈራው ፡ ነው ። ፫ አንድ ፡ ድርሻ ፡ ሁሉን ፡ እንዲያገኝ ፡ ከፀሐይ ፡ በታች ፡ በተደረገው ፡ ሁሉ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ክፉ ፡ ነው ፤ ደግሞም ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ልብ ፡ ክፋትን ፡ ትሞላለች ÷ በሕይወታቸውም ፡ ሳሉ ፡ እብደት ፡ በልባቸው ፡ ነው ÷ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሙታን ፡ ይወርዳሉ ። ፬ ያልሞተ ፡ ውሻ ፡ ከሞተ ፡ አንበሳ ፡ ይሻላልና ፡ ሰው ፡ ከሕያዋን ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ በአንድነት ፡ ቢኖር ፡ ተስፋ ፡ አለው ። ፭ ሕያዋን ፡ እንዲሞቱ ፡ ያውቃሉና ፤ ሙታን ፡ ግን ፡ አንዳች ፡ አያውቁም ፤ መታሰቢያቸውም ፡ ተረስቶአልና ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ዋጋ ፡ የላቸውም ። ፮ ፍቅራቸውና ፡ ጥላቸው ፡ ቅንዓታቸውም ፡ በአንድነት ፡ ጠፍቶአል ÷ ከፀሐይ ፡ በታችም ፡ በሚሠራው ፡ ነገር ፡ ለዘላለም ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ የላቸውም ።

፯ እግዚአብሔር ፡ ሥራህን ፡ ተቀብሎታልና ፡ ሂድ ÷ እንጀራህን ፡ በደስታ ፡ ብላ ÷ የወይን ፡ ጠጅህንም ፡ በተድላ ፡ ጠጣ ። ፰ ሁልጊዜ ፡ ልብስህ ፡ ነጭ ፡ ይሁን ፤ ቅባትም ፡ ከራስህ ፡ ላይ ፡ አይታጣ ። ፱ በሕይወትህ ÷ አንተም ፡ ከፀሐይ ፡ በታች ፡ በምትደክምበት ፡ ድካም ፡ ይህ ፡ እድል ፡ ፈንታህ ፡ ነውና ፡ ከንቱ ፡ በሆነ ፡ በሕይወትህ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ÷ ከፀሐይ ፡ በታች ፡ በሰጠህ ÷ በከንቱ ፡ ዘመንህ ፡ ሁሉ ÷ ከምትወድዳት ፡ ሚስትህ ፡ ጋር ፡ ደስ ፡ ይበልህ ። ፲ አንተ ፡ በምትሄድበት ፡ በሲኦል ፡ ሥራና ፡ አሳብ ፡ እውቀትና ፡ ጥበብ ፡ አይገኙምና ፡ እጅህ ፡ ለማድረግ ፡ የምታገኘውን ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ኃይልህ ፡ አድርግ ።

፲፩ እኔም ፡ ተመለስሁ ÷ ከፀሐይ ፡ በታችም ፡ ሩጫ ፡ ለፈጣኖች ÷ ሰልፍም ፡ ለኃያላን ÷ እንጀራም ፡ ለጠቢባን ÷ ባለጠግነትም ፡ ለአስተዋዮች ÷ ሞገስም ፡ ለአዋቂዎች ፡ እንዳልሆነ ፡ አየሁ ፤ ጊዜና ፡ እድል ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡ ይገናኙቸዋል ። ፲፪ ሰውም ፡ ጊዜውን ፡ አያውቅም ፤ በክፉ ፡ መረብ ፡

እንደ፡ ተጠመዱ፡ ዓሣዎች፥ በወጥመድም፡ እንደ፡ ተያዙ፡ ወፎች፥ እንዲሁ፡ የሰው፡ ልጆች፡ በክፉ፡ ጊዜ፡ በድንገት፡ ሲወድቅባቸው፡ ይጠመዳሉ።

፲፫፡ ከፀሐይ፡ በታችም፡ ይህን፡ ጥበብ፡ አየሁ፥ እርስዋም፡ በእኔ፡ ዘንድ፡ ታላቅ፡ መሰለችኝ። ፲፬፡ ታናሽ፡ ከተማ፡ ነበረች፥ ጥቂቶች፡ ሰዎችም፡ ነበሩባት፤ ታላቅ፡ ንጉሥም፡ መጣባት፡ ከበበትም፥ ታላቅ፡ ግንብም፡ ሠራባት። ፲፭፡ ጠቢብ፡ ድሀ፡ ሰውም፡ ተገኘባት፥ ያችንም፡ ከተማ፡ በጥበቡ፡ አዳናት፤ ያን፡ ድሀ፡ ሰው፡ ፲፮፡ ግን፡ ማንም፡ አላሰበውም። እኔም፦ ከኃይል፡ ይልቅ፡ ጥበብ፡ ትበልጣለች፤ የድሀው፡ ጥበብ፡ ግን፡ ተናቀች፡ ቃሉም፡ አልተሰማችም፡ አልሁ።

፲፯፡ በሰነፎች፡ መካከል፡ ከሚጮኽ፡ ከገዢው፡ ጩኸት፡ ይልቅ፡ የጠቢባን፡ ቃል፡ በጸጥታ፡ ፲፰፡ ትሰማለች። ከጦር፡ መሣሪያዎች፡ ይልቅ፡ ጥበብ፡ ትሻላለች፤ አንድ፡ ኃጢአተኛ፡ ግን፡ ብዙ፡ መልካምን፡ ያጠፋል።

## ምዕራፍ፡ ፲።

፩፡ የሞቱ፡ ዝንቦች፡ የተቀመመውን፡ የዘይት፡ ሽቱ፡ ያገሙታል፤ እንዲሁም፡ ትንሽ፡ ስንፍና፡ ፪፡ ጥበብንና፡ ክብርን፡ ያጠፋል። የጠቢብ፡ ልብ፡ በስተ፡ ቀኙ፡ ነው፥ የሰነፍ፡ ልብ፡ ግን፡ በስተ፡ ፫፡ ግራው፡ ነው። ደግሞም፡ ሰነፍ፡ በመንገድ፡ ሲመላለስ፡ እርሱ፡ ልብ፡ ይጐድለዋል፥ የሚያስበውም፡ ሁሉ፡ ስንፍና፡ ነው።

፬፡ ትዕግሥት፡ ታላቁን፡ ኃጢአት፡ ጸጥ፡ ያደርጋልና፡ የገዢ፡ ቍጣ፡ የተነሣብህ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ፭፡ ስፍራህን፡ አትልቀቅ። ከፀሐይ፡ በታች፡ ያየሁት፡ ክፉ፡ ነገር፡ አለ፥ እርሱም፡ ከገዢ፡ የሚ ፮፡ ወጣ፡ ስሕተት፡ ነው፤ ሰነፍ፡ በታላቅ፡ ማዕርግ፡ ተሾመ፥ ባለጠጎች፡ ግን፡ በተዋረደ፡ ስፍራ፡ ፯፡ ተቀመጡ። ባሪያዎች፡ በፈረስ፡ ላይ፡ ሲቀመጡ፡ መሳፍንትም፡ እንደ፡ ባሪያዎች፡ በምድር፡ ላይ፡ ሲሄዱ፡ አየሁ።

፰፡ ጕድጓድን፡ የሚምስ፡ ይወድቅበታል፥ ቅጥርንም፡ የሚያፈርስን፡ እባብ፡ ትነድፈዋለች። ፱፡ ድንጋይን፡ የሚፈነቅል፡ ይታመምበታል፥ እን ፲፡ ጨትንም፡ የሚፈልጥ፡ ይጐዳበታል። ብረት፡ ቢደነዝዝ፡ ሰውም፡ ባይስለው፡ ኃይልን፡ ሊያበዛ፡ ይገባዋል፤ ጥበብ፡ ግን፡ ሥራውን፡ ለማ ፲፩፡ ከናወን፡ ትጠቅመዋለች። ደጋሚ፡ ሳይደግምባት፡ እባብ፡ ብትነድፍ፡ ለደጋሚው፡ ትርፍ፡ የለውም።

፲፪፡ የጠቢብ፡ ሰው፡ የአፉ፡ ቃል፡ ሞገስ፡ ናት፤ የሰነፍ፡ ከንፈሮች፡ ግን፡ ራሱን፡ ይውጡታል። ፲፫፡ የአፉ፡ ቃል፡ መጀመሪያ፡ ስንፍና፡ ነው፥ የን ፲፬፡ ግግሩ፡ ፍጻሜም፡ ክፉ፡ እብደት፡ ነው። ሰነፍ፡ ቃሉን፡ ያበዛል፤ ሰው፡ ግን፡ የሚሆነውን፡ አያውቅም፤ ከእርሱስ፡ በኋላ፡ የሚሆነውን፡ ማን፡ ፲፭፡ ይነግረዋል? የሰነፍ፡ ሥራ፡ ያደክመዋል፡ ወደ፡ ከተማ፡ መሄድ፡ አያውቅምና።

፲፮፡ ንጉሥሽ፡ ሕፃን፡ የሆነ፥ መኳንንቶችሽም፡ ማልደው፡ የሚበሉ፥ አንቺ፡ አገር፡ ሆይ፥ ወዮልሽ! ፲፯፡ ንጉሥሽ፡ የከበረ፡ ልጅ፡ የሆነ፥ ለብርታት፡ እንጂ፡ ለስካር፡ ያይደለ፡ በጊዜ፡ የሚበሉ፡ መኳንንት፡ ያሉሽ፥ አንቺ፡ አገር፡ ሆይ፥ የተመሰገንሽ፡ ነሽ። ፲፰፡ ተግባር፡ በመፍታት፡ ጣራው፡ ይዘብጣል፥ በእጅም፡ መታከት፡ ቤት፡ ያፈስሳል። ፲፱፡ እንጀራን፡ ለሳቅ፡ የወይን፡ ጠጅንም፡ ለሕይወት፡ ደስታ፡ ያደርጉታል፥ ሁሉም፡ ለገንዘብ፡ ይገዛል። ፳፡ የሰማይ፡ ወፍ፡ ቃሉን፡ ይወስደዋልና፥ ባለ፡ ክንፎችም፡ ነገሩን፡ ይናገራሉና፡ በልብህ፡ አሳብ፡ እንኳ፡ ቢሆን፡ ንጉሥን፡ አትስደብ፥ በመኝታ፡ ቤትህም፡ ባለጠጋን፡ አትስደብ።

## ምዕራፍ፡ ፲፩።

፩፡ እንጀራህን፡ በውኃ፡ ፊት፡ ላይ፡ ጣለው፥ ከብዙ፡ ቀን፡ በኋላ፡ ታገኘዋለህና። ፪፡ ለሰባት፡ ደግሞም፡ ለስምንት፡ እድል፡ ፈንታን፡ ክፈል፥ በምድር፡ ላይ፡ የሚሆነውን፡ ክፉ፡ ነገር፡ ምን፡ እንደ፡ ሆነ፡ አታውቅምና። ፫፡ ደመናት፡ ዝናብ፡ በሞሉ፡ ጊዜ፡ በምድር፡ ላይ፡ ያፈስሱታል፤ ዛፍም፡ ወደ፡ ደቡብ፡ ወይም፡ ወደ፡ ሰሜን፡ ቢወድቅ፥ ዛፉ፡ በወደቀበት፡ ስፍራ፡ በዚያ፡ ይኖራል። ፬፡ ነፋስን፡ የሚጠባበቅ፡ አይዘራም፥ ደመናትንም፡ የሚመለከት፡ አያጭድም። ፭፡ የነፋስ፡ መንገድ፡ እንዴት፡ እንደ፡ ሆነች፡ አጥንትም፡ በእርጉዝ፡ ሆድ፡ እንዴት፡ እንድትዋደድ፡ እንደማታውቅ፥ እንዲሁም፡ ሁሉን፡ የሚሠራውን፡ የእግዚአብሔርን፡ ሥራ፡ አታውቅም።

፮፡ ወይም፡ ይህ፡ ወይም፡ ያ፡ ማናቸው፡ እንዲበቅል፡ ወይም፡ ሁለቱ፡ መልካም፡ እንዲሆኑ፡ አታውቅምና፡ በማለዳ፡ ዘርህን፡ ዝራ፥ በማታም፡ እጅህን፡ አትተው። ፯፡ ብርሃን፡ ጣፋጭ፡ ነው፡ ፀሐይንም፡ ማየት፡ ለዓይን፡ መልካም፡ ነው። ፰፡ ሰው፡ ብዙ፡ ዘመን፡ በሕይወት፡ ቢኖር፡ በሁሉም፡ ደስ፡ ይበለው፤ ሆኖም፡ የጨለማውን፡ ዘመን፡ ያስብ፥ ብዙ፡ ቀን፡ ይሆናልና። የሚመጣው፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ከንቱ፡ ነው።

፱፡ አንተ፡ ጕበዝ፥ በጕብዝናህ፡ ደስ፡ ይበልህ፥ በጕብዝናህም፡ ወራት፡ ልብህን፡ ደስ፡ ይበለው፥ በልብህም፡ መንገድ፡ ዓይኖችህም፡ በሚያዩት፡ ሂድ፡ ዱሩ፡ ግን፡ ስለዚህ፡ ነገር፡ ሁሉ፡ እግዚአብሔር፡ ወደ፡ ፍርድ፡ እንዲያመጣህ፡ እወቅ። ፲፡ ሕፃንነትና፡ ጕብዝና፡ ከንቱዎች፡ ናቸውና፡ ከልብህ፡ ኀዘንን፡ አርቅ፥ ከሰውነትህም፡ ክፉን፡ ነገር፡ አስወግድ።

## ምዕራፍ፡ ፲፪።

፩፡ የጭንቀት፡ ቀን፡ ሳይመጣ፡ በጕብዝናህ፡ ወራት፡ ፈጣሪህን፡ አስብ፤ ደስ፡ አያሰኙም፡ የምትላቸውም፡ ዓመታት፡ ሳይደርሱ፤ ፪፡ ፀሐይና፡ ብርሃን፡ ጨረቃና፡ ከዋክብትም፡ ሳይጨልሙ፥

፫፤ ደመናትም ፡ ከዝናብ ፡ በኋላ ፡ ሳይመለሱ ፤ ቤት ፡ ጠባቆች ፡ በሚንቀጠቀጡበት ÷ ኃያላን ፡ ሰዎችም ፡ በሚጎብጡበት ÷ ጥቂቶች ፡ ሆነዋልና ፡ ፈጭታዎች ፡ ሥራ ፡ በሚፈቱበት ÷ በመስኮትም ፡ ሆነው ፡ የሚመለከቱ ፡ በሚጨልሙበት ÷
፬፤ በአደባባይም ፡ ደጆቹ ፡ በሚዘጉበት ፡ ቀን ፤ የወፍጮ ፡ ድምፅ ፡ ሲላሽ ÷ ከወፍ ፡ ድምፅ ፡ የተነሣ ፡ ሰው ፡ ሲነሣ ÷ ዜማም ፡ የሚጮኹ ፡ ሴቶች ፡
፭፤ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ዝግ ፡ ሲሉ ፤ ከፍ ፡ ያለውን ፡ ደግሞ ፡ ሲፈሩ ÷ ድንጋጤም ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ ሲሆን ፤ ለውዝም ፡ ሲያብብ ÷ አንበጣም ፡ እንደ ፡ ሸክም ፡ ሲከብድ ÷ ፈቃድም ፡ ሲጠፋ ፤ ሰው ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ቤት ፡ ሲሄድ ÷ አልቃሾችም ፡
፮፤ በአደባባይ ፡ ሲዞሩ ፤ የብር ፡ ድሪ ፡ ሳይበጠስ ÷ የወርቅም ፡ ኵስኵስት ፡ ሳይሰበር ÷ ማድጋውም ፡ በምንጭ ፡ አጠገብ ፡ ሳይከሰከስ ÷ መንኰራኵ
፯፤ ሩም ፡ በጕድጓድ ፡ ላይ ፡ ሳይሰበር ÷ አፈርም ፡ ወደ ፡ ነበረበት ፡ ምድር ፡ ሳይመለስ ÷ ነፍስም ፡ ወደ ፡ ሰጠው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሳይመ
፰፤ ለስ ፡ ፈጣሪህን ፡ አስብ ። ሰባኪው ፡— ከንቱ ÷ ከንቱ ፤ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ ይላል ።

፱፤ ሰባኪውም ፡ ጠቢብ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለሕዝቡ ፡ እውቀትን ፡ አስተማረ ፤ እርሱም ፡ ብዙ ፡ ምሳ
፲፤ ሌዎችን ፡ መረመረና ፡ ፈላለገ ፡ አስማማም ። ሰባኪው ፡ ያማረውን ፡ በቅንም ፡ የተጻፈውን ፡ እውነተኛውን ፡ ቃል ፡ መርምሮ ፡ ለማግኘት ፡ ፈለገ ።

፲፩፤ የጠቢባን ፡ ቃል ፡ እንደ ፡ በሬ ፡ መውጊያ ፡ ነው ÷ የተሰበሰቡትም ፡ ከአንድ ፡ እረኛ ፡ የተሰጡት ፡ ቃላት ፡ እንደ ፡ ተቸነከሩ ፡ ችንካሮች ፡
፲፪፤ ናቸው ። ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ በላይ ÷ ልጄ ፡ ሆይ ÷ ተግሣጽን ፡ ስማ ፤ ብዙ ፡ መጻሕፍትን ፡ ማድረግ ፡ ፍጻሜ ፡ የለውም ÷ አጅግም ፡ ምርምር ፡ ሰውነትን ፡ ያደክማል ።

፲፫፤ የነገሩን ፡ ሁሉ ፡ ፍጻሜ ፡ እንስማ ፤ ይህ ፡ የሰው ፡ ሁለንተናው ፡ ነውና ፤ እግዚአብሔርን ፡ ፍራ ÷
፲፬፤ ትእዛዙንም ፡ ጠብቅ ። እግዚአብሔር ፡ ሥራን ፡ ሁሉ ፡ የተሰወረውንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ÷ መልካም ፡ ቢሆን ፡ ክፉም ፡ ቢሆን ÷ ወደ ፡ ፍርድ ፡ ያመጣዋልና ።

# መኃልየ ፡ መኃልይ ፡ ዘሰሎሞን ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ ከመዝሙር ፡ ሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ የሰሎሞን ፡ መዝሙር ።

፪፤ በአፉ ፡ መሳም ፡ ይሳመኝ ÷
ፍቅርህ ፡ ከወይን ፡ ጠጅ ፡ ይልቅ ፡ መልካም ፡ ነውና ።
፫፤ ዘይትህ ፡ መልካም ፡ መዓዛ ፡ አለው ፤
ስምህ ፡ እንደሚፈስስ ፡ ዘይት ፡ ነው ፤
ስለዚህ ፡ ደናግል ፡ ወደዱህ ።
፬፤ ሳበኝ ÷ ከአንተም ፡ በኋላ ፡ እንሮጣለን ፤
ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ አገባኝ ፤
በአንተ ፡ ደስ ፡ ይለናል ÷ ሐሤትም ፡ እናደርጋለን ፤
ከወይን ፡ ጠጅ ፡ ይልቅ ፡ ፍቅርህን ፡ እናስባለን ፤
በቅንነት ፡ ይወድዱሃል ።

፭፤ እናንተ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ቈነጃጅት ፡ ሆይ ÷ እኔ ፡ ጥቁር ፡ ነኝ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ውብ ፡ ነኝ ÷ እንደ ፡ ቄዳር ፡ ድንኳኖች ፡ እንደ ፡ ሰሎሞንም ፡ መጋረጃዎች ።
፮፤ ፀሐይ ፡ መልኬን ፡ አክስሎታልና ፡
ጥቁር ፡ ስለ ፡ ሆንሁ ፡ አትዩኝ ፤
የእናቴ ፡ ልጆች ፡ ተጣሉኝ ÷
የወይን ፡ በታዎችንም ፡ ጠባቂ ፡ አደረጉኝ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ የእኔን ፡ ወይን ፡ በታ ፡ አልጠበቅሁም ።
፯፤ ነፍሴ ፡ የወደደችህ ፡ አንተ ፡ ንገረኝ ፤
ወዴት ፡ ታሰማራለህ ? በቀትርስ ፡ ጊዜ ፡ ወዴት ፡ ትመስጋለህ ?
ስለ ፡ ምንስ ፡ ከባልንጀሮችህ ፡ መንጎች ፡ በኋላ ፡ እቅበዘበዛለሁ ?
፰፤ አንቺ ፡ በሴቶች ፡ ዘንድ ፡ የተዋብሽ ፡ ሆይ ÷
ያላወቅሽ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የመንጎችን ፡ ፍለጋ ፡ ተከትለሽ ፡ ውጪ ÷
የፍየል ፡ ግልገሎችሽንም ፡ በእረኞች ፡ ድንኳኖች ፡ አጠገብ ፡ አሰማሪ ።

፱፤ ወዳጄ ፡ ሆይ ÷ በፈርዖን ፡ ሰረገሎች ፡ እንዳለ ፡ ፈረስ ፡ መሰልሁሽ ።
፲፤ የጕንጭሽ ፡ ውበት ፡ በከበረ ፡ ሉል ÷
አንገትሽም ፡ በዕንቍ ፡ ድሪ ፡ ያማረ ፡ ነው ።
፲፩፤ ባለ ፡ ብር ፡ ጕብጕብ ፡ የሆነ ፡ የወርቅ ፡ ጠልሰም ፡ እናደርግልሻለን ።
፲፪፤ ንጉሡ ፡ በማዕዱ ፡ ሳለ ÷
የእኔ ፡ ናርዶስ ፡ መዓዛውን ፡ ሰጠ ።
፲፫፤ ውዴ ፡ ለእኔ ፡ በጡቶቼ ፡ መካከል ፡ እንደሚያርፍ ፡
እንደ ፡ ተቋጠረ ፡ ከርቤ ፡ ነው ።
፲፬፤ ውዴ ፡ ለእኔ ፡ በዓይንጋዲ ፡ ወይን ፡ በታ ፡ እንዳለ ፡
እንደ ፡ አበባ ፡ እቅፍ ፡ ነው ።
፲፭፤ ወዳጄ ፡ ሆይ ÷ እነሆ ÷ ውብ ፡ ነሽ ፤
እነሆ ÷ አንቺ ፡ ውብ ፡ ነሽ ፤
ዓይኖችሽም ፡ እንደ ፡ ርግቦች ፡ ናቸው ።
፲፮፤ ውዴ ፡ ሆይ ÷ እነሆ ÷ አንተ ፡ ውብ ፡ ነህ ÷
መልከ ፡ መልካምም ፡ ነህ ፤
አልጋችንም ፡ ለምለም ፡ ነው ።
፲፯፤ የቤታችን ፡ ሰረገላ ፡ የዝግባ ፡ ዛፍ ፡ ነው ÷
የጣሪያችንም ፡ ማዋቀሪያ ፡ የጥድ ፡ ዛፍ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፤ እኔ ፡ የሳሮን ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ የቈላም ፡ አበባ ፡ ነኝ ።
፪፤ በእሾህ ፡ መካከል ፡ እንዳለ ፡ የሱፍ ፡ አበባ ፥
እንዲሁ ፡ ወዳጄ ፡ በቈነጃጅት ፡ መካከል ፡ ናት ።
፫፤ በዱር ፡ እንዳለ ፡ እንኮይ ፥
እንዲሁ ፡ ውዴ ፡ በልጆች ፡ መካከል ፡ ነው ።
ከጥላው ፡ በታች ፡ እጅግ ፡ ወድጄ ፡ ተቀመጥሁ ፥
ፍሬውም ፡ በጕሮሮዬ ፡ ጣፋጭ ፡ ነው ።
፬፤ ወደ ፡ ወይን ፡ ጠጁም ፡ ቤት ፡ አገባኝ ፥
በእኔ ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ ዓላማውም ፡ ፍቅር ፡ ነው ።
፭፤ በዘቢብም ፡ አጽናኑኝ ፥
በእንኮይ ፡ አበረታቱኝ ፥
በፍቅሩ ፡ ተነድፌ ፡ ታምሜያለሁና ።
፮፤ ግራው ፡ ከራሴ ፡ በታች ፡ ናት ፥
ቀኙም ፡ ታቅፈኛለች ።
፯፤ እናንተ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ቈነጃጅት ፡ ሆይ ፥
እርሱ ፡ እስኪፈልግ ፡ ድረስ ፥
ፍቅርን ፡ እንዳታስነሡትና ፡ እንዳታነሣሡት ፡
በሚዳቋ ፡ በምድረ ፡ በዳም ፡ ዋላ ፡ አምላችኋ
ለሁ ።
፰፤ እነሆ ፥ የውዴ ፡ ቃል !
በተራሮች ፡ ላይ ፡ ሲዘልል ፥
በኮረብቶችም ፡ ላይ ፡ ሲወረወር ፡ ይመጣል ።
፱፤ ውዴ ፡ ሚዳቋን ፡ ወይም ፡ የዋላን ፡ እምቦሳ ፡ ይመ
ስላል ፤
እነሆ ፥ በመስኮቶች ፡ ሲጐበኝ ፥
በዓይኑ ፡ ርግብም ፡ ሲመለከት ፥
እርሱ ፡ ከቅጥራችን ፡ በኋላ ፡ ቆሞአል ።
፲፤ ውዴ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረኝ ፡—
ወዳጄ ፡ ሆይ ፥ ተነሺ ፤
ውበቴ ፡ ሆይ ፥ ነዪ ።
፲፩፤ እነሆ ፥ ክረምት ፡ አለፈ ፥
ዝናቡም ፡ አልፎ ፡ ሄደ ፤
፲፪፤ አበቦች ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ተገለጡ ፥
የዜማም ፡ ጊዜ ፡ ደረሰ ፥
የቍርዬውም ፡ ቃል ፡ በምድራችን ፡ ተሰማ ።
፲፫፤ በለሱ ፡ ጐመራ ፥ ወይኖችም ፡ አበቡ ፡
መዓዛቸውንም ፡ ሰጡ ፤
ወዳጄ ፡ ሆይ ፥ ተነሺ ፤
ውበቴ ፡ ሆይ ፥ ነዪ ።
፲፬፤ በዓለት ፡ ንቃቃትና ፡ በገደል ፡ መሸሸጊያ ፡ ያለሽ ፡
ርግብ ፡ ሆይ ፥
ቃልሽ ፡ መልካም ፡ ፊትሽም ፡ ያማረ ፡ ነውና ፡
መልክሽን ፡ አሳዪኝ ፥
ድምፅሽንም ፡ አሰሚኝ ።
፲፭፤ ወይናችን ፡ አብቦአልና ፡
የወይናችንን ፡ ቦታ ፡ የሚያጠፉትን ፡ ቀበሮች ፥
ጥቃቅኑን ፡ ቀበሮች ፡ አጥምዳችሁ ፡ ያዙልን ።
፲፮፤ ውዴ ፡ የእኔ ፡ ነው ፥ እኔም ፡ የእርሱ ፡ ነኝ ፤
በሱፍ ፡ አበባዎች ፡ መካከልም ፡ መንጋውን ፡
ያሰማራል ።
፲፯፤ ውዴ ፡ ሆይ ፥ ቀኑ ፡ እስኪነፍስ ፥
ጥላውም ፡ እስኪሸሽ ፡ ድረስ ፡ ተመለስ ፤
በቅመም ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ሚዳቋውን ፡
ወይም ፡ የዋላውን ፡ እምቦሳ ፡ ምሰል ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፤ ሌሊት ፡ በምንጣፌ ፡ ላይ ፡
ነፍሴ ፡ የወደደችውን ፡ ፈለግሁት ፤
ፈለግሁት ፡ አላገኘሁትም ።
፪፤ እነሣለሁ ፡ በከተማይቱም ፡ እዞራለሁ ፥
ነፍሴ ፡ የወደደችውን ፡
በጎዳናና ፡ በአደባባይ ፡ እፈልጋለሁ ፤
ፈለግሁት ፡ አላገኘሁትም ።
፫፤ ከተማይቱን ፡ የሚዞሩት ፡ ጠባቂዎች ፡ አገኙኝ ፤
ነፍሴ ፡ የወደደችውን ፡ አያችሁትን ? አልኋቸ
ውም ።
፬፤ ከእነርሱም ፡ ጥቂት ፡ እልፍ ፡ ብዬ ፡
ነፍሴ ፡ የወደደችውን ፡ አገኘሁት ፥ ያዝሁትም ፡
ወደ ፡ እናቴም ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ወላጅ ፡ እናቴም ፡
እልፍኝ ፡
እስካገባው ፡ ድረስ ፡ አልተውሁትም ።
፭፤ እናንተ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ቈነጃጅት ፡ ሆይ ፥
እርሱ ፡ እስኪፈልግ ፡ ድረስ ፥
ፍቅርን ፡ እንዳታስነሡትና ፡ እንዳታነሣሡት ፡
በሚዳቋ ፡ በምድረ ፡ በዳም ፡ ዋላ ፡ አምላችኋለሁ ።
፮፤ መዓዛም ፡ እንደ ፡ ከርቤና ፡ እንደ ፡ ዕጣን ፡ የሆ
ነችው ፥
ከልዩ ፡ ከነጋዴ ፡ ቅመም ፡ ሁሉ ፡ የሆነችው ፥
ይህች ፡ ከምድረ ፡ በዳ ፡ እንደ ፡ ጢስ ፡ ምሰሶ ፡
የወጣችው ፡ ማን ፡ ናት ?
፯፤ እነሆ ፥ የሰሎሞን ፡ አልጋ ፡ ናት ፤
ከእስራኤል ፡ ኃያላን ፡ ስድሳ ፡ ኃያላን ፡ በዙሪያው ፡
ናቸው ።
፰፤ ሁሉም ፡ ሰይፍ ፡ የያዙ ፡ ሰልፈኞች ፡ ናቸው ፤
በሌሊት ፡ ከሚወድቀው ፡ ፍርሃት ፡ የተነሣ ፡
ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሰይፉ ፡ በወገቡ ፡ አለ ።
፱፤ ንጉሡ ፡ ሰሎሞን ፡ መሸከሚያን ፡
ከሊባኖስ ፡ እንጨት ፡ ለራሱ ፡ አሠራ ።
፲፤ ምሰሶቹን ፡ የብር ፥ መደገፊያውንም ፡ የወርቅ ፥
መቀመጫውንም ፡ ሐምራዊ ፡ ግምጃ ፡ አደረገ ፤
ውስጡ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ቈነጃጅት ፡ ፍቅር ፡
የተለበጠ ፡ ነው ።
፲፩፤ እናንተ ፡ የጽዮን ፡ ቈነጃጅት ፥ ውጡ ፤
እናቱ ፡ በሠርጉ ፡ ቀንና ፡ በልቡ ፡ ደስታ ፡ ቀን ፡
ያደረገችለትን ፡ አክሊል ፡ ደፍቶ ፡ ንጉሥ ፡ ሰሎ
ሞንን ፡ እዩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩፤ ወዳጄ ፡ ሆይ ፥ እነሆ ፥ ውብ ፡ ነሽ ፤
እነሆ ፥ አንቺ ፡ ውብ ፡ ነሽ ፤
በዓይኑ ፡ ርግብ ፡ መሸፈኛሽ ፡ ውስጥ ፡ ዓይኖችሽ ፡
እንደ ፡ ርግቦች ፡ ናቸው ፤
ጠጕርሽ ፡ በገለዓድ ፡ ተራራ ፡ እንደሚወርድ ፡
እንደ ፡ ፍየል ፡ መንጋ ፡ ነው ።
፪፤ ጥርሶችሽ ፡ ታጥበው ፡ እንደ ፡ ተሸለቱ ፡
ሁሉም ፡ መንታ ፡ እንደ ፡ ወለዱ ፡

ከእነርሱም ፡ መካን ፡ እንደሌለባቸው ፡ መንታች ፡ ናቸው ።

፫፤ ከንፈሮችሽ ፡ እንደ ፡ ቀይ ፡ ሐር ፡ ፈትል ፡ ናቸው ፥
አፍሽም ፡ ያማረ ፡ ነው ፤
በዓይነ ፡ ርግብ ፡ መሸፈኛሽ ፡ ውስጥ ፡ ጕንጭና ፡ ጕንጭሽ ፡
እንደ ፡ ተከፈለ ፡ ሮማን ፡ ናቸው ።

፬፤ አንገትሽ ፡ ለሰልፍ ፡ ዕቃ ፡ መስቀያ ፡ እንደ ፡ ተሠራው ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፡ ግንብ ፡ ነው ፤
ሺህ ፡ ጋሻ ፡ የኃያላንም ፡ መሣሪያ ፡ ሁሉ ፡ ተንጠልጥሎበታል ።

፭፤ ሁለቱ ፡ ጡቶችሽ ፡ መንታ ፡ እንደ ፡ ተወለዱ ፥
በሱፍ ፡ አበባ ፡ መካከል ፡ እንደሚሰማሩ ፡
እንደ ፡ ሚዳቋ ፡ ግልገሎች ፡ ናቸው ።

፮፤ ቀኑ ፡ እስኪነፍስ ፡ ጥላውም ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፥
ወደ ፡ ከርቤው ፡ ተራራ ፡ ወደ ፡ ዕጣኑም ፡ ኮረብታ ፡ እሄዳለሁ ።

፯፤ ወዳጄ ፡ ሆይ ፥ ሁለንተናሽ ፡ ውብ ፡ ነው ፥
ነውርም ፡ የለብሽም ።

፰፤ ሙሽራዬ ፡ ሆይ ፥ ከሊባኖስ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ነዪ ፤
ከሊባኖስ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ነዪ ፤
ከአማና ፡ ራስ ፡ ከሳኔርና ፡ ከኤርሞን ፡ ራስ ፥
ከአንበሶች ፡ መኖሪያ ፡ ከነብሮችም ፡ ተራራ ፡ ተመልከች ።

፱፤ እኅቴ ፡ ሙሽራ ፡ ሆይ ፥ ልቤን ፡ በደስታ ፡ አሳበድሽው ፤
አንድ ፡ ጊዜ ፡ በዓይኖችሽ ፥ ከአንገትሽስ ፡ ድሪ ፡ በአንዱ ፡
ልቤን ፡ በደስታ ፡ አሳበድሽው ።

፲፤ እኅቴ ፡ ሙሽራ ፡ ሆይ ፥ ፍቅርሽ ፡ እንዴት ፡ መልካም ፡ ነው !
ፍቅርሽ ፡ ከወይን ፡ ጠጅ ፡ ይልቅ ፡ እንዴት ፡ ይሻላል !
የዘይትሽም ፡ መዓዛ ፡ ከሽቱ ፡ ሁሉ !

፲፩፤ ሙሽራዬ ፡ ሆይ ፥ ከከንፈሮችሽ ፡ ማር ፡ ይንጠበጠባል ፤
ከምላስሽ ፡ በታች ፡ ማርና ፡ ወተት ፡ አለ ፥
የልብስሽም ፡ መዓዛ ፡ እንደ ፡ ሊባኖስ ፡ ሽታ ፡ ነው ።

፲፪፤ እኅቴ ፡ ሙሽራ ፡ የተቈለፈ ፡ ገነት ፥
የተዘጋ ፡ ምንጭ ፡ የታተመም ፡ ፈሳሽ ፡ ናት ።

፲፫፤ ቡቃያሽ ፡ ሮማንና ፡ የተመረጠ ፡ ፍሬ ፥
ቆዕ ፡ ከናርዶስ ፡ ጋር ፡ ያለበት ፡ ገነት ፡ ነው ፥

፲፬፤ ናርዶስ ፡ ከቀጋ ፡ ጋር ፥ የሽቱ ፡ ሣርና ፡ ቀረፋ ፥
ከልዩ ፡ ልዩ ፡ ዕጣን ፡ ጋር ፥
ከርቤና ፡ እሬት ፡ ከክቡር ፡ ሽቱ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ።

፲፭፤ አንቺ ፡ የገነት ፡ ምንጭ ፥ የሕይወት ፡ ውኃ ፡ ጕድጓድ ፥
ከሊባኖስም ፡ የሚፈስስ ፡ወንዝ ፡ ነሽ ።

፲፮፤ የሰሜን ፡ ነፋስ ፡ ሆይ ፥ ተነሥ ፥
የደቡብም ፡ ነፋስ ፡ና ፤
በገነቴ ፡ ላይ ፡ ንፈስ ፥
ሽቱውም ፡ ይፍሰስ ፤
ውዴ ፡ ወደ ፡ ገነቱ ፡ ይግባ ፥
መልካሙንም ፡ ፍሬ ፡ ይብላ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩፤ እኅቴ ፡ ሙሽራዬ ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ ገነቴ ፡ ገባሁ ፥
ከርቤዬን ፡ ከሽቱዬ ፡ ጋር ፡ ለቀምሁ ፥
እንጀራዬን ፡ ከማሬ ፡ ጋር ፡ በላሁ ፥
የወይን ፡ ጠጄን ፡ ከወተቴ ፡ ጋር ፡ ጠጣሁ ።
ባልንጀሮቼ ፡ ሆይ ፥ ብሉ ፤
ወዳጆ ፡ ሆይ ፥ ጠጡ ፤ እስክትረኩ ፡ ድረስ ፡ ጠጡ ።

፪፤ እኔ ፡ ተኝቻለሁ ፥ ልቤ ፡ ግን ፡ ነቅቶአል ፤
የውዴ ፡ ቃል ፡ ነው ፥ እርሱም ፡ ደጁን ፡ ይመታል ፤
እኅቴ ፥ ወዳጄ ፥ ርግቤ ፥ መደምደሚያዬ ፡ ሆይ ፥
በራሴ ፡ ጠል ፥ በቈንዳላዬም ፡ የሌሊት ፡ ነጠብጣብ ፡
ሞልቶበታልና ፡ ክፈችልኝ ።

፫፤ ቀሚሴን ፡ አወለቅሁ ፤ እንዴት ፡ እለብሰዋለሁ ?
እግሬን ፡ ታጠብሁ ፤ እንዴት ፡ አሳድፈዋለሁ ?

፬፤ ውዴ ፡ እጁን ፡ በቀዳዳ ፡ ሰደደ ፥
አንጀቴም ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ታወከ ።

፭፤ ለውዴ ፡ እከፍትለት ፡ ዘንድ ፡ ተነሣሁ ፤
እጆቼ ፡ በደጁ ፡ መወርወሪያ ፡ ላይ ፡ ከርቤን ፡ አፈሰሱ ፥
ጣቶቼ ፡ ፈሳሹን ፡ ከርቤ ፡ አንጠበጠቡ ።

፮፤ ለውዴ ፡ ከፈትሁለት ፥
ውዴ ፡ ግን ፡ ፈቀቅ ፡ ብሎ ፡ አልፎ ፡ ነበር ።
ነፍሴ ፡ ከቃሉ ፡ የተነሣ ፡ ደነገጠች ፤
ፈለግሁት ፥ አላገኘሁትም ፤
ጠራሁት ፥ አልመለሰልኝም ።

፯፤ ከተማይቱን ፡ የሚዞሩት ፡ ጠባቂዎች ፡ አገኙኝ ፤
መቱኝ ፥ አቈሰሉኝም ፤
ቅጥር ፡ ጠባቂዎችም ፡ የዓይነ ፡ ርግብ ፡ መሸፈኛዬን ፡ ወሰዱት ።

፰፤ እናንተ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ቈነጃጅት ፡ ሆይ ፥ አምላችኋለሁ ፤
ውዴን ፡ ያገኛችሁት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥
እኔ ፡ ከፍቅር ፡ የተነሣ ፡ መታመሜን ፡ንገሩት ።

፱፤ አንቺ ፡ በሴቶች ፡ ዘንድ ፡ የተዋብሽ ፡ ሆይ ፥
ከሌላ ፡ ወዳጅ ፡ ይልቅ ፡ ውድሽ ፡ ማን ፡ ነው ?
ይህን ፡ የሚያህል ፡ አምለሽናልና ፡
ከሌላ ፡ ወዳጅ ፡ ይልቅ ፡ ውድሽ ፡ ማን ፡ ነው ?

፲፤ ውዴ ፡ ነጭና ፡ ቀይ ፡ ነው ፥
ከእልፍ ፡ የተመረጠ ፡ ነው ።

፲፩፤ ራሱ ፡ ምዝምዝ ፡ ወርቅ ፡ ነው ፤
ቈንዳላው ፡ የተዘረፈረፈ ፡ ነው ፥ እንደ ፡ ቁራ ፡ ጥቁረትም ፡ ጥቁር ፡ ነው ።

፲፪፤ ዓይኖቹ ፡ በሙሉ ፡ ፈሳሽ ፡ አጠገብ ፡ እንዳሉ ፡
በወተት ፡ እንደ ፡ ታጠቡ ፡ በፈሳሽ ፡ ውኃ ፡ አጠገብ ፡ እንደ ፡ ተቀመጡ ፡
እንደ ፡ ርግቦች ፡ ናቸው ።

፲፫፤ ጕንጩና ፡ ጕንጩ ፡ የሽቱ ፡ መደብ ፡
እርከን ፡ እንዳለበት ፡ እንደ ፡ ሽቱ ፡ አትክልት ፡ ናቸው ፤

ከንፈሮቹ ፡ እንደ ፡ አበቦች ፡ ናቸው ፥
የሚፈስስ ፡ ከርቤንም ፡ ያንጠበጥባሉ ።
፲፬ ፡ እጆቹ ፡ የቢረሌ ፡ ፈርጥ ፡ እንዳለበት ፡ እንደ ፡ ወርቅ ፡ ቀለበት ፡ ናቸው ፤
አካሉ ፡ ብልሃተኛ ፡ እንደ ፡ ሠራው ፡
በሰንፔር ፡ እንዳጌጠ ፡ እንደ ፡ ዝሆን ፡ ጥርስ ፡ ነው ።
፲፭ ፡ እግሮቹ ፡ በምዝምዝ ፡ ወርቅ ፡ እንደ ፡ ተመሠረቱ ፡
እንደ ፡ ዕብነ ፡ በረድ ፡ ምሰሶች ፡ ናቸው ፤
መልኩ ፡ እንደ ፡ ሊባኖስና ፡ እንደ ፡ ዝግባ ፡ ዛፍ ፡ መልካም ፡ ነው ።
፲፮ ፡ አፉ ፡ እጅግ ፡ ጣፋጭ ፡ ነው ፥ እርሱም ፡ ፈጽሞ ፡ ያማረ ፡ ነው ፤
እናንተ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ቈነጃጅት ፡ ሆይ ፥
ውዴ ፡ ይህ ፡ ነው ፥ ባልንጀራዬም ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ፡ አንቺ ፡ በሴቶች ፡ ዘንድ ፡ የተዋብሽ ፡ ሆይ ፥
ከአንቺ ፡ ጋር ፡ እንፈልገው ፡ ዘንድ ፡ ውድሽ ፡ ወዴት ፡ ሄደ ?
ውድሽስ ፡ ወዴት ፡ ፈቀቅ ፡ አለ ?
፪ ፡ ውዴ ፡ በገነቱ ፡ መንጋውን ፡ ያሰማራ ፡ ዘንድ ፡
አበባውንም ፡ ይሰበስብ ፡ ዘንድ ፡
ወደ ፡ ሽቱ ፡ መደብ ፡ ወደ ፡ ገነቱ ፡ ወረደ ።
፫ ፡ እኔ ፡ የውዴ ፡ ነኝ ፡ ውዴም ፡ የእኔ ፡ ነው ፤
በሱፉ ፡ አበባ ፡ መካከል ፡ መንጋውን ፡ ያሰማራል ።
፬ ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፥ እንደ ፡ ቴርሳ ፡ ውብ ፡ ነሽ ፥
እንደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ያማርሽ ፡ ነሽ ፤
ዓላማ ፡ ይዞ ፡ እንደ ፡ ተሰለፈ ፡ ሠራዊት ፡ ታስፈራያለሽ ።
፭ ፡ አውክውኛልና ፡ ዓይኖችሽን ፡ ከፊቴ ፡ መልሺ ፤
ጠጕርሽ ፡ ከገለዓድ ፡ እንደ ፡ ወረደ ፡ እንደ ፡ ፍየል ፡ መንጋ ፡ ነው ።
፮ ፡ ጥርሶችሽ ፡ ታጥበው ፡ እንደ ፡ ወጡ ፡
ሁሉ ፡ መንታ ፡ እንደ ፡ ወለዱ ፡
ከእነርሱም ፡ መካን ፡ እንደሌለባቸው ፡ መንጎች ፡ ናቸው ።
፯ ፡ በዓይነ ፡ ርግብ ፡ መሸፈኛሽ ፡ ውስጥ ፡ ጕንጭና ፡ ጕንጭሽ ፡
እንደ ፡ ተከፈለ ፡ ሮማን ፡ ናቸው ።
፰ ፡ ስድሳ ፡ ንግሥታት ፡ ሰማንያም ፡ ቍባቶች ፡
ቍጥር ፡ የሌላቸውም ፡ ቈነጃጅት ፡ አሉ ።
፱ ፡ ርግቤ ፡ መደምደሚያዬም ፡ አንዲት ፡ ናት ፤
ለእናትዋ ፡ አንዲት ፡ ናት ፡ ለወለደቻትም ፡ የተመረጠች ፡ ናት ።
ቈነጃጅትም ፡ አይተው ፡ አሞገሱአት ፥
ንግሥታትና ፡ ቍባቶችም ፡ አመሰገኑአት ።
፲ ፡ ይህች ፡ እንደ ፡ ማለዳ ፡ ብርሃን ፡ የምትጐበኝ ፥
እንደ ፡ ጨረቃ ፡ የተዋበች ፡ እንደ ፡ ፀሐይም ፡ የጠራች ፥
ዓላማ ፡ ይዞ ፡ እንደ ፡ ተሰለፈ ፡ ሠራዊት ፡ የምታስፈራ ፡ ማን ፡ ናት ?
፲፩ ፡ የወንዙን ፡ ዳር ፡ ልምላሜ ፡ አይ ፡ ዘንድ ፥
ወይኑ ፡ አብቦ ፡ ሮማኑም ፡ አፍርቶ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እመለከት ፡ ዘንድ ፡
ወደ ፡ ገውዝ ፡ ገነት ፡ ወረድሁ ።
፲፪ ፡ ሳላውቅ ፡ ነፍሴ ፡ በከበረው ፡ ሰረገላ ፡ ላይ ፡ አስቀመጠችኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ፡ አንቺ ፡ ሱላማጢስ ፡ ሆይ ፥ ተመለሺ ፥ ተመለሺ ፤
እናይሽ ፡ ዘንድ ፡ ተመለሺ ፥ ተመለሺ ።
በሱላማጢስ ፡ ምን ፡ ታያላችሁ ?
እርስዋ ፡ እንደ ፡ መሃናይም ፡ ዘፈን ፡ ናት ።
፪ ፡ አንቺ ፡ የመኰንን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥
እግሮችሽ ፡ በጫማ ፡ ውስጥ ፡ እንዴት ፡ ውቦች ፡ ናቸው !
ዳሌዎችሽስ ፡ በአንጥረኛ ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ተሠሩ ፡
እንደ ፡ ዕንቍዎች ፡ ይመስላሉ ።
፫ ፡ እንብርትሽ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ እንደማይጐድልበት ፡ እንደ ፡ ተነጠጠ ፡ ጽዋ ፡ ነው ፤
ሆድሽ ፡ እንደ ፡ ስንዴ ፡ ክምር ፥ በአበባም ፡ እንደ ፡ ታጠረ ፡ ነው ።
፬ ፡ ሁለቱ ፡ ጡቶችሽ ፡ እንደ ፡ ሁለቱ ፡ መንታ ፡
እንደ ፡ ሚዳቋ ፡ ግልገሎች ፡ ናቸው ።
፭ ፡ አንገትሽ ፡ እንደ ፡ ዝሆን ፡ ጥርስ ፡ ግንብ ፡ ነው ፤
ዓይኖችሽ ፡ በሐሴቦን ፡ ውስጥ ፡ በባትረቢ ፡ በር ፡ አጠገብ ፡
እንደ ፡ ውኃ ፡ ኵሬዎች ፡ ናቸው ፤
አፍንጫሽ ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ አፋዛዥ ፡ እንደሚመለከት ፡
እንደ ፡ ሊባኖስ ፡ ግንብ ፡ ነው ።
፮ ፡ ራስሽ ፡ እንደ ፡ ቀርሜሎስ ፡ ተራራ ፡ በላይሽ ፡ ነው ፤
የራስሽም ፡ ጠጕር ፡ እንደ ፡ ሐምራዊ ፡ ሐር ፡ ነው ፤
ንጉሡ ፡ በሹርባው ፡ ታስሮአል ።
፯ ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፥ እንዴት ፡ የተዋብሽ ፡ ነሽ !
እንዴትስ ፡ ደስ ፡ ታሰኛለሽ !
፰ ፡ ይህ ፡ ቁመትሽ ፡ የዘንባባ ፡ ዛፍ ፡ ይመስላል ፥
ጡቶችሽም ፡ የወይን ፡ ዘለላ ፡ ይመስላሉ ።
፱ ፡ ወደ ፡ ዘንባባው ፡ ዛፍ ፡ እወጣለሁ ፡
ጫፎችዋንም ፡ እይዛለሁ ፡ አልሁ ፤
ጡቶችሽ ፡ እንደ ፡ ወይን ፡ ዘለላ ፡
የአፍንጫሽም ፡ ሽቱ ፡ እንደ ፡ እንኮይ ፡ ናቸው ።
፲ ፡ ጕሮሮሽ ፡ ለወዳጄ ፡ እየጣፈጠ ፡ እንደሚገባ ፥
የተኙትን ፡ ከንፈሮች ፡ ይናገሩ ፡ ዘንድ ፡ እንደሚያደርግ ፥
እንደ ፡ ማለፊያ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ነው ።
፲፩ ፡ እኔ ፡ የውዴ ፡ ነኝ ፥ የእርሱም ፡ ምኞት ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ነው ።
፲፪ ፡ ውዴ ፡ ሆይ ፥ ና ፥ ወደ ፡ መስክ ፡ እንውጣ ፡ በመንደሮችም ፡ እንደር ።
፲፫ ፡ ወደ ፡ ወይኑ ፡ ቦታ ፡ ማልደን ፡ እንሂድ ፤
ወይኑ ፡ አብቦ ፡ አበባውም ፡ ፍሬ ፡ አንዠርግጎ ፡
ሮማኑም ፡ አፍርቶ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንይ ፤

በዚያ ፡ ውዴን ፡ እሰጥሃለሁ ።
፲፬፤ ትርንጎዎች ፡ መዓዛን ፡ ሰጡ ፤
መልካሞች ፡ ፍሬዎች ፡ ሁሉ ፥
አሮጌው ፡ ከአዲሱ ፡ ጋር ፥ በደጃችን ፡ አሉ ፤
ውዴ ፡ ሆይ ፥ ሁሉን ፡ ለአንተ ፡ ጠበቅሁልህ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩፤ አንተ ፡ የእናቴን ፡ ጡት ፡ እንደ ፡ ጠባ ፡ እንደ ፡ ወንድሜ ፡ ምነው ፡ በሆንህ !
በሜዳ ፡ ባገኘሁህ ፡ ጊዜ ፡ በሳምሁህ ፥ ማንም ፡ ባልናቀኝም ፡ ነበር ።
፪፤ መርቼ ፡ ወደ ፡ እናቴ ፡ ቤት ፡ ባገባሁህ ፥
በዚያም ፡ አንተ ፡ ባስተማርከኝ ፤
እኔም ፡ ከመልካሙ ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡ ከሮማኔም ፡ ውኃ ፡ ባጠጣሁህ ፡ ነበር ።
፫፤ ግራው ፡ ከራሴ ፡ በታች ፡ በሆነች ፡ ቀኙም ፡ ባቀፈችኝ ፡ ነበር ።
፬፤ እናንተ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ቈነጃጅት ፡ ሆይ ፥
እርሱ ፡ እስኪፈልግ ፡ ድረስ ፡ ፍቅርን ፡ እንዳታስነሡት ፡
እንዳታነሣሡትም ፡ አምላችኋለሁ ።
፭፤ በውድዋ ፡ ላይ ፡ ተደግፋ ፡ ከምድረ ፡ በዳ ፡ የምትወጣ ፡ ይህች ፡ ማን ፡ ናት ?
ከእንኮይ ፡ በታች ፡ አስነሣሁህ ፤
በዚያ ፡ እናትህ ፡ወለደችህ ፥
በዚያም ፡ ወላጅ ፡ እናትህ ፡ አማጠችህ ።
፮፤ እንደ ፡ ማኅተም ፡ በልብህ ፥
እንደ ፡ ማኅተም ፡ በክንድህ ፡ አኑረኝ ፤
ፍቅር ፡ እንደ ፡ ሞት ፡ የበረታች ፡ ናትና ፥
ቅንዓትም ፡ እንደ ፡ ሲኦል ፡ የጨከነች ፡ ናትና ።
ፍንጣሪዋ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ፍንጣሪ ፥
እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነበልባል ፡ ነው ።
፯፤ ብዙ ፡ ውኃ ፡ ፍቅርን ፡ ያጠፋት ፡ ዘንድ ፡ አይችልም ፥
ፈሳሾችም ፡ አያሰጥሙአትም ፤
ሰው ፡ የቤቱን ፡ ሀብት ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ፍቅር ፡ ቢሰጥ ፡ ፈጽሞ ፡ ይንቁታል ።
፰፤ እኛ ፡ ጡት ፡ የሌላት ፡ ታናሽ ፡ እኅት ፡ አለችን ፤
ስለ ፡ እርስዋ ፡ በሚናገሩባት ፡ ቀን ፡
ለእኅታችን ፡ ምን ፡ እናድርግላት ?
፱፤ እርስዋ ፡ ቅጥር ፡ ብትሆን ፡ የብር ፡ ግንብ ፡ በላይዋ ፡ እንሠራለን ፤
ደጅም ፡ ብትሆን ፡ በዝግባ ፡ ሳንቃ ፡ እንከብባታለን ።
፲፤ እኔ ፡ ቅጥር ፡ ነኝ ፡ ጡቶቼም ፡ እንደ ፡ ግንብ ፡ ናቸው ፤
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በፊቱ ፡ ሰላምን ፡ እንደምታገኝ ፡ ሆንሁ ።
፲፩፤ ለሰሎሞን ፡ በብኤላሞን ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ ነበረው ፤
የወይኑን ፡ ቦታ ፡ ለጠባቂዎች ፡ አከራየው ፤
ሰው ፡ ሁሉ ፡ ለፍሬው ፡ ሺህ ፡ ብር ፡ ያመጣለት ፡ ነበር ።
፲፪፤ ለእኔ ፡ ያለኝ ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ በፊቴ ፡ ነው ፤
ሰሎሞን ፡ ሆይ ፥ ሺሁ ፡ ለአንተ ፥
ሁለት ፡ መቶውም ፡ ፍሬውን ፡ ለሚጠብቁ ፡ ይሆናል ።
፲፫፤ በገነቱ ፡ የምትቀመጪ ፡ ሆይ ፥
ባልንጀሮች ፡ የአንችን ፡ ቃል ፡ ያደምጣሉ ፤
ቃልሽን ፡ አሰሚኝ ።
፲፬፤ ውዴ ፡ ሆይ ፥ ፍጠን ፤
በቅመም ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ሚዳቋን ፡
ወይም ፡ የዋላን ፡ እምቦሳ ፡ ምሰል ።

# ት ን ቢ ተ ፡ ኢ ሳ ይ ያ ስ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ በዖዝያንና ፡ በኢዮአታም ፡ በአካዝና ፡ በሕዝቅያስ ፡ ዘመን ፡ ስለ ፡ ይሁዳና ፡ ስለ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ያየው ፡ የአሞጽ ፡ ልጅ ፡ የኢሳይያስ ፡ ራእይ ።
፪፤ እግዚአብሔር ፡ ተናግሮአልና ፡ ሰማያት ፡ ስሙ ፥ ምድርም ፡ አድምጪ ፤ ልጆችን ፡ ወለድሁ ፡ አሳደግሁም ፥ እነርሱም ፡ ዐመፁብኝ ።
፫፤ በሬ ፡ የገዢውን ፡ አህያም ፡ የጌታውን ፡ ጋጣ ፡ አወቀ ፤ እስራኤል ፡ ግን ፡ አላወቀም ፥ ሕዝቤም ፡ አላስተዋለም ።
፬፤ ኃጢአተኛ ፡ ወገንና ፡ በደል ፡ የተሞላበት ፡ ሕዝብ ፥ የክፉዎች ፡ ዘር ፥ ርኵሰትን ፡ የምታደርጉ ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ ወዮላችሁ ! እግዚአብሔርን ፡ ትተዋል ፡ የእስራኤልንም ፡ ቅዱስ ፡ አቃልለዋል ፡ ወደ ፡ ኋላቸውም ፡ እየሄዱ ፡ ተለይተዋል ።
፭፤ ደግሞስ ፡ ዓመፃ ፡ እየጨመራችሁ ፡ ለምን ፡ ገና ፡ ትቀሠፋላችሁ ? ራስ ፡ ሁሉ ፡ ለሕመም ፡ ልብም ፡ ሁሉ ፡ ለድካም ፡ ሆኖአል ።
፮፤ ከእግር ፡ ጫማ ፡ አንሥቶ ፡ እስከ ፡ ራስ ፡ ድረስ ፡ ጤና ፡ የለውም ፤ ቍስልና ፡ እበጥ ፡ የሚመግልም ፡ ነው ፤ አልፈረጠም ፥ አልተጠገነም ፥ በዘይትም ፡ አልለዘበም ።
፯፤ ምድራችሁ ፡ ባድማ ፡ ናት ፤ ከተሞቻችሁ ፡ በእሳት ፡ ተቃጠሉ ፤ እርሻችሁንም ፡ በፊታችሁ ፡ ሌሎች ፡ ይበሉታል ፤ ባዕድ ፡ እንዳፈረሳት ፡

በዚያ ፡ ውዴን ፡ እሰጥሃለሁ ።
፲፬ ትርንጎዎች ፡ መዓዛን ፡ ሰጡ ፤
መልካሞች ፡ ፍሬዎች ፡ ሁሉ ፥
አሮጌው ፡ ከአዲሱ ፡ ጋር ፥ በደጃችን ፡ አሉ ፤
ውዴ ፡ ሆይ ፥ ሁሉን ፡ ለአንተ ፡ ጠበቅሁልህ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ አንተ ፡ የእናቴን ፡ ጡት ፡ እንደ ፡ ጠባ ፡ እንደ ፡ ወንድሜ ፡ ምነው ፡ በሆንህ !
በሜዳ ፡ በገኘሁህ ፡ ጊዜ ፡ በሳምሁህ ፥ ማንም ፡ ባልናቀኝም ፡ ነበር ።
፪ መርቼ ፡ ወደ ፡ እናቴ ፡ ቤት ፡ በገባሁ ፥
በዚያም ፡ አንተ ፡ ባስተማርከኝ ፤
እኔም ፡ ከመልካሙ ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡ ከሮማኔም ፡ ውኃ ፡ በጠጣሁህ ፡ ነበር ።
፫ ግራው ፡ ከራሴ ፡ በታች ፡ በሆነች ፡ ቀኙም ፡ በቀፈችኝ ፡ ነበር ።
፬ እናንተ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ቈነጃጅት ፡ ሆይ ፥
እርሱ ፡ እስኪፈልግ ፡ ድረስ ፡ ፍቅርን ፡ እንዳታስነሡት ፡
እንዳታነሣሡትም ፡ አምላችኋለሁ ።
፭ በውድዋ ፡ ላይ ፡ ተደግፋ ፡ ከምድረ ፡ በዳ ፡ የምትወጣ ፡ ይህች ፡ ማን ፡ ናት ?
ከእንኮይ ፡ በታች ፡ አስነሣሁህ ፤
በዚያ ፡ እናትህ ፡ ወለደችህ ፥
በዚያም ፡ ወላጅ ፡ እናትህ ፡ አማጠችህ ።
፮ እንደ ፡ ማኅተም ፡ በልብህ ፥
እንደ ፡ ማኅተም ፡ በክንድህ ፡ አኑረኝ ፤
ፍቅር ፡ እንደ ፡ ሞት ፡ የበረታች ፡ ናትና ፥
ቅንዓትም ፡ እንደ ፡ ሲኦል ፡ የጨከነች ፡ ናትና ።
ፍንጣሪዋ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ፍንጣሪ ፥
እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነበልባል ፡ ነው ።
፯ ብዙ ፡ ውኃ ፡ ፍቅርን ፡ ያጠፉት ፡ ዘንድ ፡ አይችልም ፥
ፈሳሾችም ፡ አያሰጥሙትም ፤
ሰው ፡ የቤቱን ፡ ሀብት ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ፍቅር ፡ ቢሰጥ ፡ ፈጽሞ ፡ ይንቁታል ።
፰ እኛ ፡ ጡት ፡ የሌላት ፡ ታናሽ ፡ እኅት ፡ አለችን ፤
ስለ ፡ እርስዋ ፡ በሚናገሩባት ፡ ቀን ፡
ለእኅታችን ፡ ምን ፡ እናድርግላት ?
፱ እርስዋ ፡ ቅጥር ፡ ብትሆን ፡ የብር ፡ ግንብ ፡ በላይዋ ፡ እንሠራለን ፤
ደጅም ፡ ብትሆን ፡ በዝግባ ፡ ሳንቃ ፡ እንከብባታለን ።
፲ እኔ ፡ ቅጥር ፡ ነኝ ፡ ጡቶቼም ፡ እንደ ፡ ግንብ ፡ ናቸው ፤
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በፊቱ ፡ ሰላምን ፡ እንደምታገኝ ፡ ሆንሁ ።
፲፩ ለሰሎሞን ፡ በብኤላሞን ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ ነበረው ፤
የወይኑን ፡ ቦታ ፡ ለጠባቂዎች ፡ አከራየው ፤
ሰው ፡ ሁሉ ፡ ለፍሬው ፡ ሺህ ፡ ብር ፡ ያመጣለት ፡ ነበር ።
፲፪ ለእኔ ፡ ያለኝ ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ በፊቴ ፡ ነው ፤
ሰሎሞን ፡ ሆይ ፥ ሺሁ ፡ ለአንተ ፥
ሁለቱ ፡ መቶውም ፡ ፍሬውን ፡ ለሚጠብቁ ፡ ይሆናል ።
፲፫ በገነቱ ፡ የምትቀመጪ ፡ ሆይ ፥
ባልንጀሮች ፡ የአንችን ፡ ቃል ፡ ያደምጣሉ ፤
ቃልሽን ፡ አሰሚኝ ።
፲፬ ውዴ ፡ ሆይ ፥ ፍጠን ፤
በቅመም ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ሚዳቋን ፡
ወይም ፡ የዋላን ፡ እምቦሳ ፡ ምሰል ።

# ትንቢተ ፡ ኢሳይያስ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ በዖዝያንና ፡ በኢዮአታም ፡ በአካዝና ፡ በሕዝቅያስ ፡ ዘመን ፡ ስለ ፡ ይሁዳና ፡ ስለ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ያየው ፡ የአሞጽ ፡ ልጅ ፡ የኢሳይያስ ፡ ራእይ ።

፪ እግዚአብሔር ፡ ተናግሮአልና ፡ ሰማያት ፡ ስሙ ፥ ምድርም ፡ አድምጪ ፤ ልጆችን ፡ ወለድሁ ፡ አሳደግሁም ፥ እነርሱም ፡ ዐመፁብኝ ።
፫ በሬ ፡ የገዢውን ፡ አህያም ፡ የጌታውን ፡ ጋጣ ፡ አወቀ ፤ እስራኤል ፡ ግን ፡ አላወቀም ፥ ሕዝቤም ፡ አላስተዋለም ።
፬ ኃጢአተኛ ፡ ወገንና ፡ በደል ፡ የተሞላበት ፡ ሕዝብ ፥ የክፉዎች ፡ ዘር ፥ ርኵሰትን ፡ የምታደርጉ ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ ወዮላችሁ ! እግዚአብሔርን ፡ ትተዋል ፡ የእስራኤልንም ፡ ቅዱስ ፡ አቃልለዋል ፡ ወደ ፡ ኋላቸውም ፡ እየሄዱ ፡ ተለይተዋል ።
፭ ደግሞስ ፡ ዓመፃ ፡ እየጨመራችሁ ፡ ለምን ፡ ገና ፡ ትቀሠፋላችሁ ? ራስ ፡ ሁሉ ፡ ለሕመም ፡ ልብም ፡ ሁሉ ፡ ለድካም ፡ ሆኖአል ።
፮ ከእግር ፡ ጫማ ፡ አንሥቶ ፡ እስከ ፡ ራስ ፡ ድረስ ፡ ጤና ፡ የለውም ፤ ቍስልና ፡ እበጥ ፡ የሚመግልም ፡ ነው ፤ አልፈረጠም ፥ አልተጠገነም ፥ በዘይትም ፡ አልለዘበም ።
፯ ምድራችሁ ፡ ባድማ ፡ ናት ፤ ከተሞቻችሁ ፡ በእሳት ፡ ተቃጠሉ ፤ እርሻችሁንም ፡ በፊታችሁ ፡ ሌሎች ፡ ይበሉታል ፤ ባዕድ ፡ እንዳፈረሳት ፡

፰ ምድር፡ በድማ፡ ሆነች። የጽዮንም፡ ሴት፡ ልጅ፡ በወይን፡ ቦታ፡ እንዳለ፡ ዳስ፥ በዱባ፡ አትክልትም፡ ውስጥ፡ እንዳለ፡ ጎጆ፥ እንደ፡ ተከበበችም፡ ከተማ፡ ሆና፡ ቀረች። ፱ የሠራዊት፡ ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ ዘርን፡ ባያስቀርልን፡ ኖሮ፥ እንደ፡ ሰዶም፡ በሆንን፡ እንደ፡ ገሞራም፡ በመሰልን፡ ነበር።

፲ እናንተ፡ የሰዶም፡ አለቆች፡ ሆይ፥ የእግዚአብሔርን፡ ቃል፡ ስሙ፤ እናንተ፡ የገሞራ፡ ሕዝብ፡ ሆይ፥ የአምላካችንን፡ ሕግ፡ አድምጡ። ፲፩ የመሥዋዕታችሁ፡ ብዛት፡ ለእኔ፡ ምን፡ ይጠቅመኛል? ይላል፡ እግዚአብሔር፤ የሚቃጠለውን፡ የአውራ፡ በግ፡ መሥዋዕትንና፡ የፍሪዳን፡ ስብ፡ ጠግቤያለሁ፤ የበሬና፡ የበግ፡ ጠቦት፡ የአውራ፡ ፍየልም፡ ደም፡ ደስ፡ አያሰኘኝም። ፲፪ በእኔ፡ ፊት፡ ልትታዩ፡ ብትመጡ፡ ይህን፡ የመቅደሴን፡ አደባባይ፡ መርገጣችሁን፡ ከእጃችሁ፡ የሚሻ፡ ማን፡ ነው? ፲፫ ምናምንቴውን፡ ቍርባን፡ ጨምራችሁ፡ አታምጡ፤ ዕጣን፡ በእኔ፡ ዘንድ፡ አስጸያፊ፡ ነው፤ መባቻችሁንና፡ ሰንበታችሁን፡ በጉባኤም፡ መሰብሰባችሁን፡ አልወድድም፤ በደልንም፡ የተቀደሰውንም፡ ጉባኤ፡ አልታገሥም። ፲፬ መባቻችሁንና፡ በዓላቶቻችሁን፡ ነፍሴ፡ ጠልታለች፤ ሸክም፡ ሆነውብኛል፥ ልታገሣቸውም፡ ደክሜያለሁ። ፲፭ እጃችሁንም፡ ወደ፡ እኔ፡ ብትዘረጉ፡ ዓይኔን፡ ከእናንተ፡ እሰውራለሁ፥ ልመናንም፡ ብታበዙ፡ አልሰማችሁም፤ እጆቻችሁ፡ ደም፡ ተሞልተዋል። ፲፮ ታጠቡ፡ ሰውነታችሁንም፡ አንጹ፤ የሥራችሁን፡ ክፋት፡ ከዓይኔ፡ ፊት፡ አስወግዱ፤ ክፉ፡ ማድረግን፡ ተዉ፥ ፲፯ መልካም፡ መሥራትን፡ ተማሩ፥ ፍርድን፡ ፈልጉ፥ የተገፋውን፡ አድኑ፥ ለድሀ፡ አደጉ፡ ፍረዱለት፡ ስለ፡ መበለቲቱም፡ ተምዋገቱ።

፲፰ ኑና፡ እንዋቀስ፡ ይላል፡ እግዚአብሔር፤ ኀጢአታችሁ፡ እንደ፡ አለላ፡ ብትሆን፡ እንደ፡ አመዳይ፡ ትነጻለች፤ እንደ፡ ደምም፡ ብትቀላ፡ እንደ፡ ባዘቶ፡ ትጠራለች። ፲፱ እሺ፡ ብትሉ፡ ለእኔም፡ ብትታዘዙ፥ የምድርን፡ በረከት፡ ትበላላችሁ፤ ፳ እንቢ፡ ብትሉ፡ ግን፡ ብታምፁም፥ ሰይፍ፡ ይበላችኋል፤ የእግዚአብሔር፡ አፍ፡ ይህን፡ ተናግሮአልና።

፳፩ ፍርድ፡ሞልቶበት፡ የነበረ፡ የታመነችይቱ፡ ከተማ፡ እንዴት፡ ጋለሞታ፡ ሆነች! ጽድቅ፡ አድሮበት፡ ነበር፥ አሁን፡ ግን፡ ገዳዮች፡ አሉባት። ፳፪ ብርሽ፡ ወደ፡ ዝገት፡ ተለወጠ፤ የወይን፡ ጠጅሽ፡ ከውኃ፡ ጋር፡ ተደባለቀ። ፳፫ አለቆችሽ፡ ዓመፀኞችና፡ የሌቦች፡ ባልንጀሮች፡ ሆኑ፤ ሁሉ፡ ጉቦ፡ ይወድዳሉ፥ ዋጋም፡ ለማግኘት፡ ይሮጣሉ፤ ለድሀ፡ አደጉ፡ አይፈርዱም፥ የመበለቲቱም፡ ሙግት፡ ወደ፡ እነርሱ፡ አይደርስም።

፳፬ ስለዚህ፡ የእስራኤል፡ ኃያል፡ የሠራዊት፡ ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፦ በጠላቶቼ፡ ላይ፡ ቍጣዬን፡ እፈጽማለሁ፥ የሚቋቋሙኝንም፡ እበቀላለሁ። ፳፭ እጄንም፡ በአንቺ፡ ላይ፡ አመጣለሁ፥ ዝገትሽንም፡ በጣም፡ አነጻለሁ፥ ቆርቆሮሽንም፡ ሁሉ፡ አወጣለሁ፤ ፳፮ ፈራጆችሽንም፡ እንደ፡ ቀድሞ፡ አማካሪዎችሽንም፡ እንደ፡ መጀመሪያው፡ ጊዜ፡ መልሼ፡ አስነሣለሁ፤ ከዚያም፡ በኋላ፡ የጽድቅ፡ ከተማ፡ የታመነችም፡ ከተማ፡ ተብለሽ፡ ትጠሪያለሽ። ፳፯ ጽዮን፡ በፍርድ፡ ከእርስዋም፡ የሚመለሱ፡ በጽድቅ፡ ይድናሉ። ፳፰ በደለኞችና፡ ኀጢአተኞች፡ ግን፡ በአንድነት፡ ይሰበራሉ፥ እግዚአብሔርንም፡ የሚተዉ፡ ይጠፋሉ። ፳፱ በወደዳችኋት፡ የአድባር፡ ዛፍ፡ ታፍራላችሁና፥ ስለ፡ መረጣችኋትም፡ አትክልት፡ እፍረት፡ ይይዛችኋልና፤ ፴ ቅጠልዋ፡ እንደ፡ ረገፈ፡ ዛፍ፥ ውኃም፡ እንደሌለበት፡ አትክልት፡ ትሆናላችሁና። ፴፩ ኀይለኛውም፡ እንደ፡ ተልባ፡ ጭረት፥ ሥራውም፡ እንደ፡ ጠለሸት፡ ይሆናል፤ አብረውም፡ ይቃጠላሉ፡ እነርሱንም፡ የሚያጠፋ፡ የለም።

## ምዕራፍ፡ ፪።

፩ የአሞጽ፡ ልጅ፡ ኢሳይያስ፡ ስለ፡ ይሁዳና፡ ስለ፡ ኢየሩሳሌም፡ ያየው፡ ቃል።

፪ በዘመኑም፡ ፍጻሜ፡ የእግዚአብሔር፡ ቤት፡ ተራራ፡ በተራሮች፡ ራስ፡ ላይ፡ ጸንቶ፡ ይቆማል፥ ከኮረብቶችም፡ በላይ፡ ከፍ፡ ከፍ፡ ይላል፥ አሕዛብም፡ ሁሉ፡ ወደ፡ እርሱ፡ ይሰበሰባሉ። ፫ ሕግ፡ ከጽዮን፡ የእግዚአብሔርም፡ ቃል፡ ከኢየሩሳሌም፡ ይወጣልና፡ ብዙዎች፡ አሕዛብ፡ ሄደው፦ ኑ፥ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ ተራራ፥ ወደ፡ ያዕቆብ፡ አምላክ፡ ቤት፡ እንውጣ፤ እርሱም፡ መንገዱን፡ ያስተምረናል፥ በጎዳናውም፡ እንሄዳለን፡ ይላሉ። ፬ በአሕዛብም፡ መካከል፡ ይፈርዳል፥ በብዙ፡ አሕዛብም፡ ላይ፡ ይበይናል፤ ሰይፋቸውንም፡ ማረሻ፥ ጦራቸውንም፡ ማጭድ፡ ለማድረግ፡ ይቀጠቅጣሉ፤ ሕዝብም፡ በሕዝብ፡ ላይ፡ ሰይፍ፡ አያነሣም፥ ሰልፍም፡ ከእንግዲህ፡ ወዲህ፡ አይማሩም።

፭ እናንተ፡ የያዕቆብ፡ ቤት፡ ሆይ፥ ኑ፥ በእግዚአብሔር፡ ብርሃን፡ እንሂድ። ፮ ሕዝብህን፡ የያዕቆብን፡ ቤት፡ ትተሃልና፤ ይኸውም፡ የምሥራቅን፡ ሰዎች፡ አመል፡ ስለ፡ ተሞሉ፥ እንደ፡ ፍልስጥኤማውያንም፡ ምዋርተኞች፡ ስለ፡ ሆኑ፥ ከባዕድ፡ ልጆችም፡ ጋር፡ ስለ፡ ተባበሩ፡ ነው። ፯ ምድራቸው፡ በብርና፡ በወርቅ፡ ተሞልታለች፥ ለመዛግብቶቻቸውም፡ ፍጻሜ፡ የለውም፤ ምድራቸውም፡ ደግሞ፡ በፈረሶች፡ ተሞልታለች፥ ለሰረገሎቻቸውም፡ ፍጻሜ፡ የለውም። ፰ ምድራቸው፡ ደግሞ፡ በጣዖታት፡ ተሞልታለች፤ ጣቶቻቸውም፡ ላደረጉት፡ ለእጃቸው፡ ሥራ፡ ይሰግዳሉ። ፱ ታናሹም፡ ሰው፡ ዝቅ፡ ብሎአል፥ ጨዋውም፡ ተዋርዶአል፤ ኀጢአታቸውንም፡ ይቅር፡ አትበላቸው። ፲ ከእግዚአብሔር፡ ማስደንገጥና፡ ከግርማው፡ ክብር፡ የተነሣ፡ ወደ፡ ድንጋይ፡ ዋሻ፡ ግባ፥ በመሬትም፡

፲፩ ውስጥ፡ተሸሸግ። ከፍ፡ያለችውም፡የሰው፡
ዓይን፡ትዋረዳለች፥የሰዎችም፡ኵራት፡ትወ
ድቃለች፥በዚያም፡ቀን፡እግዚአብሔር፡
ብቻውን፡ከፍ፡ከፍ፡ይላል።
፲፪ የሠራዊት፡ጌታ፡የእግዚአብሔር፡ቀን፡
በትዕቢተኛውና፡በኵራተኛው፡ሁሉ፡ላይ፡
ከፍ፡ባለውም፡ላይ፡ይሆናል፥እርሱም፡
፲፫ ይዋረዳል፤ደግሞም፡በረጅሙ፡ከፍ፡ባለ
ውም፡በሊባኖስ፡ዝግባ፡ሁሉ፡ላይ፥በባሳ
፲፬ ንም፡ዛፍ፡ሁሉ፡ላይ፥በረጅሙም፡ተራራ፡
ሁሉ፡ላይ፥ከፍ፡ባለውም፡ኮረብታ፡ሁሉ፡
፲፭ ላይ፥በረጅሙም፡ግንብ፡ሁሉ፡ላይ፥በተመ
፲፮ ሸገውም፡ቅጥር፡ሁሉ፡ላይ፥በተርሴስም፡
መርከብ፡ሁሉ፡ላይ፥በሚያማምሩ፡ጣዖታ
፲፯ ትም፡ሁሉ፡ላይ፡ይሆናል። ሰውም፡ሁሉ፡
ይዋረዳል፥የሰውም፡ኵራት፡ይወድቃል፥
በዚያም፡ቀን፡እግዚአብሔር፡ብቻ፡ከፍ፡ከፍ፡
፲፰ ይላል። ጣዖቶቻቸውም፡ሁሉ፡ፈጽመው፡
፲፱ ይጠፋሉ። እግዚአብሔርም፡ምድርን፡ያና
ውጥ፡ዘንድ፡በተነሣ፡ጊዜ፡ሰዎች፡ከማስደን
ገጡና፡ከግርማው፡ክብር፡የተነሣ፡ወደ፡ድን
ጋይ፡ዋሻና፡ወደ፡ምድር፡ንቃቃት፡ውስጥ፡
፳ ይገባሉ። በዚያም፡ቀን፡ሰው፡ይሰግድላቸው፡
ዘንድ፡ያበጁአቸውን፡የብሩንና፡የወርቁን፡ጣዖ
ቶቹን፡ለፍልፈልና፡ለሌሊት፡ወፍ፡ይጥላል።
፳፩ እግዚአብሔርም፡ምድርን፡ያናውጥ፡ዘንድ፡
በተነሣ፡ጊዜ፡ከማስደንገጡና፡ከግርማው፡
ክብር፡የተነሣ፡ወደ፡ድንጋይ፡ዋሻና፡ወደ፡
፳፪ ተሰነጠቁ፡ዓለቶች፡ውስጥ፡ይገባሉ። እስት
ንፋሱ፡በአፍንጫው፡ያለበትን፡ሰው፡ተዉት፤
እርሱ፡ስለ፡ምን፡ይቈጠራል?

## ምዕራፍ፡፫።

፩ እነሆ፥የሠራዊት፡ጌታ፡እግዚአብሔር፡ከኢ
የሩሳሌምና፡ከይሁዳ፡ድጋፍንና፡ብርታትን፥
የእንጀራን፡ድጋፍ፡ሁሉ፡የውኃውንም፡
፪ ድጋፍ፡ሁሉ፥ኃያሉንም፥ተዋጊውንም፥
ፈራጁንም፥ነቢዩንም፥ምዋርተኛውንም፥
፫ ሽማግሌውንም፥የአምሳ፡አለቃውንም፥ከበ
ርቴውንም፥አማካሪውንም፥ብልሁንም፡ሠራ
ተኛ፥አስማት፡አዋቂውንም፡ይነቅላል።
፬ አለቆቻቸው፡እንዲሆኑ፡ብላቴኖችን፡አስነሣ
፭ ባቸዋለሁ፥ሕፃናቶችም፡ይገዙአቸዋል። ሕዝ
ቡም፥ሰው፡በሰው፡ላይ፡ሰውም፡በባልንጀ
ራው፡ላይ፥ይገፋፋል፤ብላቴናውም፡በሽ
ማግሌው፡ላይ፡የተጠቃውም፡በከበርቴው፡
፮ ላይ፡ይኰራል። ሰውም፡በአባቱ፡ቤት፡
ውስጥ፡ወንድሙን፡ይዞ፦አንተ፡ልብስ፡
አለህ፡አለቃም፡ሁንልን፡ይህችም፡በድማ፡
፯ ከእጅህ፡በታች፡ትሁን፡ሲለው፥በዚያ፡ቀን፡
ድምፁን፡ከፍ፡አድርጎ፦እኔ፡በቤቴ፡ውስጥ፡
እንጀራ፡ወይም፡ልብስ፡የለኝምና፡ባለ፡መድ
ኃኒት፡አልሆንም፤በሕዝቡም፡ላይ፡አለቃ፡
፰ አታደርጉኝም፡ይላል። የክብሩን፡ዓይን፡ያስ
ቈጡ፡ዘንድ፡ምላሳቸውና፡ሥራቸው፡በእ
ግዚአብሔር፡ላይ፡ነውና፡ኢየሩሳሌም፡ተፈ
ታች፡ይሁዳም፡ወደቀ። የፊታቸውም፡እፍ ፱
ረት፡ይመሰክርባቸዋል፤እንደ፡ሰዶምም፡ኃጢ
አታቸውን፡ያወራሉ፥አይሠውሩአትም። በራ
ሳቸው፡ላይ፡ክፉ፡ነገርን፡ሠርተዋልና፡ለነፍ
ሳቸው፡ወዮ! የሥራቸውን፡ፍሬ፡ይበላሉና፡ ፲
ጻድቁን፦መልካም፡ይሆንልሃል፡በሉት።
እንደ፡እጁ፡ሥራ፡ፍዳው፡ይደረግበታልና፡ ፲፩
ለበደለኛ፡ወዮ! ክፉም፡ደርሶበታል። ሕዝ ፲፪
ቤንስ፡አስገባሪዎቻቸው፡ይገፍፉአቸዋል፥
አስጨናቂዎችም፡ይሠለጥኑባቸዋል። ሕዝቤ፡
ሆይ፥የመሩአችሁ፡ያስቱአችኋል፡የምትሄ
ዱበትንም፡መንገድ፡ያጠፋሉ።
እግዚአብሔር፡ለፍርድ፡ተነሥቶአል፡በሕ ፲፫
ዝቡም፡ላይ፡ሊፈርድ፡ቆሞአል። እግዚአ ፲፬
ብሔር፡ከሕዝቡ፡ሽማግሌዎችና፡ከአለቆቻ
ቸው፡ጋር፡ይፋረዳል፤የወይኑን፡ቦታ፡የጨ
ረሳችሁ፡እናንተ፡ናችሁ፤ከድሆች፡የበዘበዛ
ችሁት፡በቤታችሁ፡አለ፤ሕዝቤንም፡ለምን፡ ፲፭
ታደቅቁአቸዋላችሁ?የድሆችንስ፡ፊት፡ለምን፡
ትፈጫላችሁ? ይላል፡የሠራዊት፡ጌታ፡እግ
ዚአብሔር።
ደግሞም፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡አለ፦ ፲፮
የጽዮን፡ቈነጃጅት፡ኰርተዋልና፥አንገታቸ
ውንም፡እያሰገጉ፡በዓይናቸውም፡እያጣቀሱ፥
ፈንጠርም፡እያሉ፥በእግራቸውም፡እያቃ
ጨሉ፡ይሄዳሉና፡ስለዚህ፡ጌታ፡የጽዮንን፡ቈነ ፲፯
ጃጅት፡እናት፡በቡሀነት፡ይመታል፥እግዚአ
ብሔርም፡ኀፍረተ፡ሥጋቸውን፡ይገልጣል።
በዚያም፡ቀን፡ጌታ፡የእግር፡አልቦውን፡ ፲፰
ክብር፥መርበብንም፥ጨረቃ፡የሚመስለው
ንም፡ጌጥ፥የጆሮ፡እንጥልጥሉንም፥አንባ ፲፱
ሩንም፥መሸፈኛውንም፥ቀጸላውንም፥ሰን ፳
ሰለቱንም፥መቀነቱንም፥የሽቱውንም፡ዕቃ፥
አሸንክታቡንም፥የእጅና፡የአፍንጫ፡ቀለበ ፳፩
ቱንም፥የዓመት፡በዓልንም፡ልብስ፥መጐ ፳፪
ናጸፊያውንም፥ልግምበገላውንም፥ከረጢቱ
ንም፥መስተዋቱንም፥ከጥሩ፡በፍታ፡የተ ፳፫
ሠራውንም፡ልብስ፥ራስ፡ማሰሪያውንም፥
ዓይነ፡ርግቡንም፡ያስወግዳል። እንዲህም፡ ፳፬
ይሆናል፤በሽቱ፡ፋንታ፡ግማት፥በመታጠ
ቂያውም፡ፋንታ፡ገመድ፥ጠጕርንም፡በመ
ንቀስ፡ፋንታ፡ቡሀነት፥በመጐናጸፊያ፡ፋንታ፡
ማቅ፥በውበትም፡ፋንታ፡ጠባሳ፡ይሆናል።
ጕልማሶችሽ፡በሰይፍ፥ኃያላንሽም፡በውጊያ፡ ፳፭
ይወድቃሉ። በሮችዋ፡ያዝናሉ፡ያለቅሱማል፤ ፳፮
እርስዋም፡ብቻዋን፡በምድር፡ላይ፡ትቀመጣ
ለች።

## ምዕራፍ፡፬።

በዚያም፡ቀን፡ሰባት፡ሴቶች፦የገዛ፡እንጀ ፩
ራችንን፡እንበላለን፡የገዛ፡ልብሳችንንም፡እን
ለብሳለን፤ስምህ፡ብቻ፡በእኛ፡ላይ፡ይጠራ፥

መሰደብችንንም ፡ አርቅ ፡ ብለው ፡ አንዱን ፡
ወንድ ፡ ይይዙታል ።
፪ በዚያም ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጥቋጥ ፡
ለጌጥና ፡ ለክብር ፡ ይሆናል ፥ ከእስራኤልም ፡
ወገን ፡ ላመለጡ ፡ ሰዎች ፡ የምድሪቱ ፡ ፍሬ ፡
፫፡፬ ለትምክሕትና ፡ ለውበት ፡ ይሆናል ። ጌታም ፡
የጽዮንን ፡ ቈነጃጅት ፡ እድፍ ፡ ባጠበ ፡ ጊዜ ፥
የኢየሩሳሌምንም ፡ ደም ፡ በፍርድ ፡ መንፈስና ፡
በሚያቃጥል ፡ መንፈስ ፡ ከመካከልዋ ፡ ባነጻ ፡
ጊዜ ፥ በጽዮን ፡ የቀረ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ የተ
ረፈ ፥ በኢየሩሳሌም ፡ ለሕይወት ፡ የተጻፈ ፡
፭ ሁሉ ፥ ቅዱስ ፡ ይባላል ። እግዚአብሔርም ፡
በጽዮን ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ባለ ፡ ማደሪያ ፡ ሁሉ ፡
በጉባኤአቸውም ፡ ላይ ፡ በቀን ፡ ዳመናንና ፡
ጢስን ፡ በሌሊትም ፡ የሚቃጠለውን ፡ የእሳት ፡
ብርሃን ፡ ይፈጥራል ፤ በክብርም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡
፮ መጋረጃ ፡ ይሆናል ። በቀን ፡ ከሙቀት ፡ ለጥላ ፥
ከዐውሎ ፡ ነፋስና ፡ ከዝናብም ፡ ለመጠጊያና ፡
ለመሸሸጊያ ፡ ጎጆ ፡ ይሆናል ።

ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ አሁን ፡ ስለ ፡ ወዳጄና ፡ ስለ ፡ ወይኑ ፡ ቦታው ፡
ለወዳጄ ፡ ቅኔ ፡ እቀኛለሁ ። ለወዳጄ ፡ በፍሬያ
ማው ፡ ኮረብታ ፡ ላይ ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ ነበረው ።
፪ በዙሪያው ፡ ቈፈረ ፥ ድንጋዮችንም ፡ ለቅሞ ፡
አወጣ ፥ ምርጥ ፡ የሆነውንም ፡ አረግ ፡ ተከለ
በት ፥ በመካከሉም ፡ ግንብ ፡ ሠራ ፥ ደግሞም ፡
የመጥመቂያ ፡ ጕድጓድ ፡ ማሰበት ፤ ወይንንም ፡
ያፈራ ፡ ዘንድ ፡ ተማመነ ፥ ዳሩ ፡ ግን ፡ ሆምጣጣ ፡
ፍሬ ፡ አፈራ ።
፫ አሁንም ፡ እናንተ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የምት
ኖሩ ፡ የይሁዳ ፡ ሰዎችም ፡ ሆይ ፥ በእኔና ፡ በወ
፬ ይኑ ፡ ቦታዬ ፡ መካከል ፡ እስኪ ፡ ፍረዱ ። ለወ
ይኔ ፡ ያላደረግሁለት ፥ ከዚህ ፡ ሌላ ፡ አደርግ
ለት ፡ ዘንድ ፡ የሚገባኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ወይ
ንን ፡ ያፈራል ፡ ብዬ ፡ ስተማመን ፡ ስለ ፡ ምን ፡
፭ ሆምጣጣ ፡ ፍሬ ፡ አፈራ ? አሁንም ፡ በወይኔ ፡
ላይ ፡ የማደርገውን ፡ እነግራችኋለሁ ፤ አጥሩን ፡
እነቅላለሁ ፥ ለማሰማርያም ፡ ይሆናል ፤ ቅጥሩ
ንም ፡ አፈርሳለሁ ፥ ለመረገጫም ፡ ይሆናል ።
፮ በድጋ ፡ አደርገዋለሁ ፤ አይቈረጥም ፥ አይኰ
ተኰትም ፤ ኵርንችትና ፡ እሾህ ፡ ይበቅልበታል ፤
ዝናብንም ፡ እንዳያዘንቡበት ፡ ዳመናዎችን ፡
፯ አዝዛለሁ ። የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ወይን ፡ ቦታ ፡ እርሱ ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ነው ፥
የደስታውም ፡ አትክልት ፡ የይሁዳ ፡ ሰዎች ፡
ናቸው ፤ ፍርድን ፡ ተስፋ ፡ ያደርግ ፡ ነበር ፥ እነ
ሆም ፥ ደም ፡ ማፍሰስ ፡ ሆነ ፤ ጽድቅንም ፡ ይተ
ማመን ፡ ነበር ፥ እነሆም ፥ ጩኸት ፡ ሆነ ።
፰ ስፍራ ፡ እስከማይቀር ፡ ድረስ ፡ እናንተም ፡
በምድር ፡ ላይ ፡ ብቻችሁን ፡ እስክትቀመጡ ፡
ድርስ ፥ ቤትን ፡ ከቤት ፡ ጋር ፡ ለሚያያይዙ ፡
እርሻንም ፡ ከእርሻ ፡ ጋር ፡ ለሚያቀራርቡ ፡ ወዮ
፱ ላቸው ! የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በጆ
ሮዬ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— በእውነት ፡ ብዙ ፡ ታላ
ቅና ፡ መልካም ፡ ቤት ፡ በድጋ ፡ ይሆናል ፥ የሚ
ቀመጥበትም ፡ አይገኝም ። ከወይኑ ፡ ቦታ ፡
፲ አሥር ፡ ጥማድ ፡ በሬ ፡ ካረሰው ፡ አንድ ፡ የባ
ዶስ ፡ መስፈሪያ ፡ ብቻ ፡ ይወጣል ፤ አንድ ፡ የቆ
ሮስ ፡ መስፈሪያ ፡ ዘር ፡ አንድ ፡ የኢፍ ፡ መስፈ
ሪያ ፡ ብቻ ፡ ይሰጣል ።
፲፩ ስካርን ፡ ለመከተል ፡ በጥዋት ፡ ለሚማልዱ ፥
የወይን ፡ ጠጅም ፡ እስኪያቃጥላቸው ፡ እስከ ፡
ሌሊት ፡ ድረስ ፡ ለሚዘገዩ ፡ ወዮላቸው ! መሰን
፲፪ ቆና ፡ በገና ፡ ከበሮና ፡ እምቢልታም ፡ የወይን ፡
ጠጅም ፡ በግብዣቸው ፡ አለ ፤ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ሥራ ፡ ግን ፡ አልተመለከቱም ፥ እጁም ፡
ያደረገችውን ፡ አላስተዋሉም ።
፲፫ ስለዚህ ፡ ሕዝቤ ፡ ወደ ፡ ምርኮ ፡ ሄዱ ፥ ጌታን ፡
አላወቁትምና ፤ ከበርቴዎቻቸውም ፡ ተራቡ ፥
፲፬ ሕዝባቸውም ፡ ተጠሙ ። ሲኦልም ፡ ሆድዋን ፡
አስፍታለች ፥ አፍዋንም ፡ ያለ ፡ ልክ ፡ ከፍታ
ለች ፤ ከበርቴዎቻቸውና ፡ አዛውንቶቻቸው ፡
ባለጠጎቻቸውም ፡ ደስተኞቻቸውም ፡ ወደ ፡ እር
፲፭ ስዋ ፡ ይወርዳሉ ። ሰውም ፡ ይጐሰቍላል ፥
ሰውም ፡ ይዋረዳል ፥ የትዕቢተኞችም ፡ ዓይን ፡
፲፮ ትዋረዳለች ፤ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡
ግን ፡ በፍርድ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎአል ፥ ቅዱሱም ፡
፲፯ አምላክ ፡ በጽድቅ ፡ ተቀድሶአል ። የበግ ፡ ጠቦ
ቶች ፡ በማሰማርያቸው ፡ ውስጥ ፡ ይሰማራሉ ፥
እንግዶችም ፡ የሰቡትን ፡ በድጋ ፡ ይበላሉ ።
፲፰ በደልን ፡ በምናምንቴ ፡ ገመድ ፥ ኃጢአት
ንም ፡ በሰረገላ ፡ ማሰሪያ ፡ ወደ ፡ ራሳቸው ፡ ለሚ
፲፱ ስቡ ፡— እናይ ፡ ዘንድ ፡ ይቸኵል ፥ ሥራውንም ፡
ያፋጥን ፤ እናውቃትም ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤል ፡
ቅዱስ ፡ ምክር ፡ ትቅረብ ፥ ትምጣ ፡ ለሚሉ ፡
ወዮላቸው !
፳ ክፉውን ፡ መልካም ፡ መልካሙን ፡ ክፉ ፡
ለሚሉ ፥ ጨለማውን ፡ ብርሃን ፡ ብርሃኑንም ፡
ጨለማ ፡ ለሚያደርጉ ፥ ጣፋጩን ፡ መራራ ፡
መራራውንም ፡ ጣፋጭ ፡ ለሚያደርጉ ፡ ወዮላ
ቸው !
፳፩ በዓይናቸው ፡ ጥበበኞች ፡ በነፍሳቸውም ፡ አስ
ተዋዮች ፡ ለሆኑ ፡ ወዮላቸው !
፳፪ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ለመጠጣት ፡ ኃያላን ፡ የሚያ
ሰክረውንም ፡ ለማደባለቅ ፡ ጨካኞች ፡ ለሆኑ ፤
፳፫ በደለኛውን ፡ ስለ ፡ ጉቦ ፡ ጻድቅ ፡ ለሚያደርጉ ፥
የጻድቁንም ፡ ጽድቅ ፡ ለሚያስወግዱበት ፡ ወዮ
ላቸው !
፳፬ ስለዚህ ፡ የእሳት ፡ ወላፈን ፡ ቃርሚያን ፡ እን
ደሚበላ ፥ እብቅም ፡ በነበልባል ፡ ውስጥ ፡ እን
ደሚጠፋ ፥ እንዲሁ ፡ የእነርሱ ፡ ሥር ፡ የበሰ
በሰ ፡ ይሆናል ፡ ቡቃያቸውም ፡ እንደ ፡ ትቢያ ፡
ይበንናል ፤ የሠራዊትን ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ሕግ ፡ ጥለዋልና ፥ የእስራኤልም ፡ ቅዱስ ፡
፳፭ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ አቃልለዋልና ። ስለዚህ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ነድዶ
አል ፡ እጁንም ፡ በላያቸው ፡ ዘርግቶ ፡ መትቶ

አቸዋል ፤ ተራሮችም ፡ ተንቀጠቀጡ ÷ ሬሳቸ
ውም ፡ በአደባባይ ፡ መካከል ፡ እንደ ፡ ጕድፍ ፡
ሆኖአል ። በዚህም ፡ ሁሉ ፡ እንኳ ፡ ቍጣው ፡
አልተመለሰችም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ እጁ ፡ ገና ፡ ተዘ
ርግታ ፡ ትኖራለች ።

፳፮ ለአሕዛብም ፡ በሩቅ ፡ ምልክትን ፡ ያቆማል ÷
ከምድርም ፡ ዳርቻ ፡ በፉጨት ፡ ይጠራቸዋል ፤
እነሆም ÷ እየተጣደፉ ፡ ፈጥነው ፡ ይመጣሉ ።
፳፯ ደካማና ፡ ስንኩል ፡ የለባቸውም ÷ የሚያንቀላ
ፋና ፡ የሚተኛም ፡ የለም ፤ የወገባቸውም ፡ መቀ
ነት ፡ አይፈታም ÷ የጫማቸውም ፡ ማዘቢያ ፡ አይ
፳፰ በጠስም ። ፍላጾቻቸው ፡ ተስለዋል ÷ ቀስቶቻ
ቸውም ፡ ሁሉ ፡ ተለጥጠዋል ፤ የፈረሶቻቸውም ፡
ኰቴ ፡ እንደ ፡ ቡላድ ፡ የሰረገሎቻቸውም ፡ መን
ኰራኵር ፡ እንደ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ይቈጠ
፳፱ ራል ። ጩኸታቸው ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ነው ÷
እንደ ፡ አንበሳ ፡ ደቦሎችም ፡ ያገሣሉ ፤ ንጥቂያ
ንም ፡ ይዘው ፡ ያገሣሉ ÷ ይወስዱትማል ÷ የሚ
፴ ያድንም ፡ የለም ። በዚያም ፡ ቀን ፡ እንደ ፡
ባሕር ፡ መትመም ፡ ይተምሙባቸዋል ፤ ወደ ፡
ምድርም ፡ ቢመለከቱ ÷ እነሆ ÷ ጨለማና ፡
መከራ ፡ አለ ፤ ብርሃንም ፡ በደመናዎችዋ ፡
ውስጥ ፡ ጨልሞአል ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ንጉሡ ፡ ዖዝያን ፡ በሞተበት ፡ ዓመት ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ በረጅምና ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡
ተቀምጦ ፡ አየሁት ÷ የልብሱም ፡ ዘርፍ ፡ መቅ
፪ ደሱን ፡ ሞልቶት ፡ ነበር ። ሱራፌልም ፡ ከእ
ርሱ ፡ በላይ ፡ ቆመው ፡ ነበር ÷ ለእያንዳንዱም ፡
ስድስት ፡ ክንፍ ፡ ነበረው ፤ በሁለት ፡ ክንፍ ፡
ፊቱን ፡ ይሸፍን ፡ ነበር ÷ በሁለቱም ፡ ክንፍ ፡ እግሮ
ቹን ፡ ይሸፍን ፡ ነበር ÷ በሁለቱም ፡ ክንፍ ፡ ይበር ፡
፫ ነበር ። አንዱም ፡ ለአንዱ ፡— ቅዱስ ÷ ቅዱስ ÷
ቅዱስ ÷ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤
ምድር ፡ ሁሉ ፡ ከክብሩ ፡ ተሞልታለች ፡ እያለ ፡
፬ ይጮኽ ፡ ነበር ። የመድረኩም ፡ መሠረት ፡ ከጮ
ዋኺው ፡ ድምፅ ፡ የተነሣ ፡ ተናወጠ ÷ ቤቱንም ፡
፭ ጢስ ፡ ሞላበት ። እኔም ፡— ከንፈሮቼ ፡ የረከሱ
ብኝ ፡ ሰው ፡ በመሆኔ ÷ ከንፈሮቻቸውም ፡ በረከ
ሱባቸው ፡ ሕዝብ ፡ መካከል ፡ በመቀመጤ ፡ ዓይ
ኖቼ ፡ የሠራዊትን ፡ ጌታ ፡ ንጉሡን ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ ስለ ፡ አዩ ፡ ጠፍቻለሁና ፡ ወዮልኝ ፤ አልሁ ።
፮ ከሱራፌልም ፡ አንዱ ፡ እየበረረ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡
መጣ ÷ በእጁም ፡ ከመሠዊያው ፡ በጕጠት ፡
፯ የወሰደው ፡ ፍም ፡ ነበረ ። አፌንም ፡ ዳሰሰበ
ትና ፡— እነሆ ÷ ይህ ፡ ከንፈሮችህን ፡ ነክቶአል ፤
በደልህም ፡ ከአንተ ፡ ተወገደ ÷ ኀጢአትህም ፡
፰ ተሰረየልህ ፡ አለኝ ። የጌታንም ፡ ድምፅ ፡—
ማንን ፡ እልካለሁ ? ማንስ ፡ ይሄድልናል ? ሲል ፡
ሰማሁ ። እኔም ፡— እነሆኝ ÷ እኔን ፡ ላከኝ ፡
፱ አልሁ ። እርሱም ፡— ሂድ ÷ ይህን ፡ ሕዝብ ፡—
መስማትን ፡ ትሰማላችሁ ፡ አታስተውሉምም ፤
ማየትንም ፡ ታያላችሁ ፡ አትመለከቱምም ፡ በላ
፲ ቸው ። በዓይናቸው ፡ እንዳያዩ ÷ በጆሮአቸ
ውም ፡ እንዳይሰሙ ÷ በልባቸውም ፡ እንዳያስ
ተውሉ ÷ ተመልሰውም ፡ እንዳይፈወሱ ÷ የዚ
ህን ፡ ሕዝብ ፡ ልብ ፡ አደንድን ÷ ጆሮአቸውንም ፡
አደንቍር ÷ ዓይናቸውንም ፡ ጨፍን ፡ አለኝ ።
፲፩ እኔም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡
ነው ? አልሁ ። እርሱም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡
አለ ፡— ከተሞች ፡ የሚኖርባቸውን ፡ አጥተው ፡
እስኪፈርሱ ፡ ድረስ ÷ ቤቶችም ፡ ሰው ፡ አልባ ፡
እስኪሆኑ ፡ ምድርም ፡ ፈጽሞ ፡ በድማ ፡ ሆና ፡
፲፪ እስክትቀር ፡ ድረስ ÷ እግዚአብሔርም ፡ ሰዎ
ችን ፡ እስኪያርቅ ÷ በምድርም ፡ መካከል ፡
ውድማው ፡ መሬት ፡ እስኪበዛ ፡ ድረስ ፡ ነው ።
፲፫ በእርስዋም ፡ ዘንድ ፡ አሥረኛ ፡ እጅ ፡ ቀርቶ ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ ይቃጠላል ፤ በተ
ቈረጡ ፡ ጊዜ ፡ ጕቶቻቸው ፡ እንደ ፡ ቀሩ ፡ እንደ ፡
ግራርና ፡ እንደ ፡ ኮምበል ፡ ዛፍ ፡ ሆኖ ÷ ጕቶው ፡
የተቀደሰ ፡ ዘር ፡ ይሆናል ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በዖዝ
ያን ፡ ልጅ ፡ በኢዮአታም ፡ ልጅ ፡ በአካዝ ፡
ዘመን ፡ የሶርያ ፡ ንጉሥ ፡ ረአሶን ፡ የእስራኤልም ፡
ንጉሥ ፡ የሮሜልዩ ፡ ልጅ ፡ ፋቁሔ ፡ ኢየሩሳሌ
ምን ፡ ሊወጉ ፡ ወጡ ÷ ሊያሸንፉአትም ፡ አል
፪ ቻሉም ። ለዳዊትም ፡ ቤት ፡— ሶርያ ፡ ከኤፍ
ሬም ፡ ጋር ፡ ተባብረዋል ፡ የሚል ፡ ወሬ ፡ ተነ
ገረ ፤ የእርሱም ፡ ልብ ፡ የሕዝቡም ፡ ልብ ፡ የዱር ፡
ዛፍ ፡ በነፋስ ፡ እንድትናወጥ ፡ ተናወጠ ።
፫ እግዚአብሔርም ፡ ኢሳይያስን ፡ አለው ፡—
አንተና ፡ ልጅህ ፡ ያሱብ ፡ አካዝን ፡ ትገናኙት ፡
ዘንድ ፡ በልብስ ፡ አጣቢው ፡ እርሻ ፡ መንገድ ፡
ወዳለው ፡ ወደ ፡ ላይኛው ፡ የኩሬ ፡ መስኖ ፡ ጫፍ ፡
፬ ውጡ ፤ እንዲህም ፡ በለው ፡— ተጠበቅ ÷
ዝምም ፡ በል ፤ ስለ ፡ እነዚህ ፡ ስለሚጤሱ ፡ ስለ ፡
ሁለት ፡ የእንጨት ፡ ጠለሸቶች ÷ ስለ ፡ ሶርያና ፡
ስለ ፡ ረአሶን ፡ ስለ ፡ ሮሜልዩም ፡ ልጅ ፡ ቍጣ ፡
፭ ፡ ፮ አትፍራ ÷ ልብህም ፡ አይድከም ። ሶርያና ፡
ኤፍሬም ፡ የሮሜልዩም ፡ ልጅ ፡— ወደ ፡ ይሁዳ ፡
እንውጣ ፡ እናስጨንቀውም ÷ እንስበረውም ÷
የጣብኤልንም ፡ ልጅ ፡ እናንግሥበት ፡ ብለው ፡
፯ ክፉት ፡ ስለ ፡ መከሩብህ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— ይህ ፡ ምክር ፡ አይጸናምና ፡
፰ አይሆንም ። የሶርያ ፡ ራስ ፡ ደማስቆ ፡ ነው ÷
የደማስቆም ፡ ራስ ፡ ረአሶን ፡ ነው ፤ በስድሳ ፡
አምስት ፡ ዓመት ፡ ውስጥ ፡ ኤፍሬም ፡ ይሰበበ
ራልና ፡ ሕዝብ ፡ አይሆንም ፤ የኤፍሬምም ፡
፱ ራስ ፡ ሰማርያ ፡ ነው ÷ የሰማርያም ፡ ራስ ፡ የሮ
ሜልዩ ፡ ልጅ ፡ ነው ። ባታምኑ ፡ አትጸኑም ።
፲ እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፡ አካዝን ፡ እንዲህ ፡
፲፩ ብሎ ፡ ተናገረው ፡— ከጥልቁ ፡ ወይም ፡ ከከፍ
ታው ፡ ቢሆን ፡ ከአምላክህ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
፲፪ ምልክትን ፡ ለምን ። አካዝም ፡— አልለምንም ÷
እግዚአብሔርንም ፡ አልፈታተንም ፡ አለ ።

፲፫ እርሱም፡ አለ፡— እናንተ፡ የዳዊት፡ ቤት፡ ሆይ፥ ስሙ፤ በሰው፡ ሰውን፡ ማድከማችሁ፡ ቀላል፡ ነውን? አምላኬን፡ ደግሞ፡ የምታደክሙ፤ ፲፬ ስለዚህ፡ ጌታ፡ ራሱ፡ ምልክት፡ ይሰጣችኋል፤ እነሆ፥ ድንግል፡ ትፀንሳለች፥ ወንድ፡ ልጅም፡ ትወልዳለች፥ ስሙንም፡ አማኑኤል፡ ብላ፡ ትጠራዋለች። ፲፭ ክፉን፡ ለመጥላት፡ መልካሙንም፡ ለመምረጥ፡ ሲያውቅ፡ ቅቤና፡ ማር፡ ይበላል። ፲፮ ሕፃኑ፡ ክፉን፡ ለመጥላት፡ መልካሙን፡ ለመምረጥ፡ ሳያውቅ፡ የፈራሃቸው፡ የሁለቱ፡ ነገሥታት፡ አገር፡ ባድማ፡ ትሆናለች። ፲፯ እግዚአብሔርም፡ ኤፍሬም፡ ከይሁዳ፡ ከተለየበት፡ ቀን፡ ጀምሮ፡ ያልመጣውን፡ ዘመን፡ በአንተና፡ በሕዝብህ፡ በአባትህም፡ ቤት፡ ላይ፡ ያመጣል፤ እርሱም፡ የአሦር፡ ንጉሥ፡ መምጣት፡ ነው።

፲፰ በዚያም፡ ቀን፡ እንዲህ፡ ይሆናል፤ እግዚአብሔር፡ በግብጽ፡ ወንዝ፡ ዳርቻ፡ ያለውን፡ ዝምብ፡ በአሦርም፡ አገር፡ ያለውን፡ ንብ፡ በፉጨት፡ ይጠራል። ፲፱ ይመጡማል፥ እነርሱም፡ ሁሉ፡ በበረሀ፡ ሸለቆ፡ በድንጋይም፡ ዋሻ፡ ውስጥ፡ በእሾህ፡ ቍጥቋጦ፡ ሁሉ፡ ላይ፡ በማሰማርያውም፡ ሁሉ፡ ላይ፡ ይሰፍራሉ።

፳ በዚያም፡ ቀን፡ እግዚአብሔር፡ ከወንዙ፡ ማዶ፡ በተከራየው፡ ምላጭ፡ በአሦር፡ ንጉሥ፡ የራሱንና፡ የእግሩን፡ ጠጕር፡ ይላጨዋል፤ ምላጩም፡ ጢሙን፡ ደግሞ፡ ይበላል።

፳፩ በዚያም፡ ቀን፡ እንዲህ፡ ይሆናል፤ ሰው፡ አንዲት፡ ጊደርን፡ ሁለት፡ በጎችንም፡ ያሳድጋል፤ ፳፪ ከሚሰጡትም፡ ወተት፡ ብዛት፡ የተነሣ፡ ቅቤ፡ ይበላል፤ በአገሪቱም፡ መካከል፡ የቀረ፡ ሁሉ፡ ቅቤና፡ ማር፡ ይበላል።

፳፫ በዚያም፡ ቀን፡ እንዲህ፡ ይሆናል፤ ሺህ፡ ብር፡ የተገመተ፡ ሺህ፡ የወይን፡ ግንድ፡ በነበረበት፡ ስፍራ፡ ሁሉ፡ ለኵርንችትና፡ ለእሾህ፡ ይሆናል። ፳፬ ኵርንችትና፡ እሾህ፡ በምድር፡ ሁሉ፡ ላይ፡ ነውና፡ በፍላጻና፡ በቀስት፡ ወደዚያ፡ ይገባሉ። ፳፭ በመቈፈርያም፡ ወደ፡ ተቈፈሩ፡ ኮረብቶች፡ ሁሉ፡ ከኵርንችትና፡ እሾህ፡ ፍርሃት፡ የተነሣ፡ ወደዚያ፡ አትሄድም፤ ነገር፡ ግን፡ የበሬ፡ ማሰማርያና፡ የበግ፡ መረገጫ፡ ይሆናል።

## ምዕራፍ፡ ፰።

፩ እግዚአብሔርም፡— ታላቅ፡ ሰሌዳ፡ ወስደህ፡— ምርኮ፡ ፈጠነ፥ ብዝበዛ፡ ቸኰለ፡ ብለህ፡ ፪ በሰው፡ ፊደል፡ ጻፍበት። የታመኑትን፡ ሰዎች፡ ካህኑን፡ ኦርዮንና፡ የበራክዩን፡ ልጅ፡ ዘካርያስን፡ ፫ ምስክሮች፡ አድርግልኝ፡ አለኝ። ወደ፡ ነቢይቱም፡ ቀረብሁ፤ እርስዋም፡ ፀነሰች፡ ወንድ፡ ልጅንም፡ ወለደች። ፬ እግዚአብሔርም፡— ሕፃኑ፡ አባቱንና፡ እናቱን፡ መጥራት፡ ሳያውቅ፡ የደማስቆን፡ ሀብትና፡ የሰማርያን፡ ምርኮ፡ በአሦር፡ ንጉሥ፡ ፊት፡ ይወስዳልና፡ ስሙን፡— ምርኮ፡ ፈጠነ፥ ብዝበዛ፡ ቸኰለ፡ ብለህ፡ ጥራው፡ አለኝ።

፭ እግዚአብሔርም፡ ደግሞ፡ ተናገረኝ፡ እንዲህም፡ አለኝ፡— ፮ ይህ፡ ሕዝብ፡ በቀስታ፡ የሚሄደውን፡ የሰሊሆምን፡ ውኃ፡ ጠልቶአልና፥ ረአሶንንና፡ የሮሜልዩንም፡ ልጅ፡ ወዶአልና፡ ፯ ስለዚህ፥ እነሆ፥ እግዚአብሔር፡ ብርቱና፡ ብዙ፡ የሆነውን፡ የወንዝ፡ ውኃ፥ የአሦርን፡ ንጉሥና፡ ክብሩን፡ ሁሉ፥ ያመጣባቸዋል፤ መስኖውንም፡ ሁሉ፡ ሞልቶ፡ ይወጣል፥ በዳሩም፡ ሁሉ፡ ላይ፡ ይፈስሳል፤ ፰ እየጐረፈም፡ ወደ፡ ይሁዳ፡ ይገባል፤ እያጥለቀለቀም፡ ያልፋል፥ እስከ፡ አንገትም፡ ይደርሳል፤ አማኑኤል፡ ሆይ፥ የክንፉ፡ መዘርጋት፡ የአገርህን፡ ስፋት፡ ትሞላለች።

፱ አሕዛብ፡ ሆይ፥ እወቁና፡ ደንግጡ፤ እናንተም፡ ምድራችሁ፡ የራቀ፡ ሁሉ፥ አድምጡ፤ ታጠቁ፥ ደንግጡ፤ ታጠቁ፥ ደንግጡ። ፲ ተመከከሩ፥ ምክራችሁም፡ ይፈታል፤ ቃሉን፡ ተናገሩ፥ ቃሉም፡ አይጸናም፤ እግዚአብሔር፡ ከእኛ፡ ጋር፡ ነውና። ፲፩ እግዚአብሔርም፡ በጽኑ፡ እጅ፡ እንዲህ፡ ተናገረኝ፥ በዚህም፡ ሕዝብ፡ መንገድ፡ እንዳልሄድ፡ አስጠነቀቀኝ፥ እንዲህም፡ አለኝ፡— ፲፪ ይህ፡ ሕዝብ፡— ዱለት፡ ነው፡ በሚሉት፡ ሁሉ፡— ዱለት፡ ነው፡ አትበሉ፤ መፈራታቸውንም፡ አትፍሩ፥ አትደንግጡ። ፲፫ ነገር፡ ግን፡ የሠራዊትን፡ ጌታ፡ እግዚአብሔርን፡ ቀድሱት፤ የሚያስፈራችሁና፡ የሚያስደነግጣችሁም፡ እርሱ፡ ይሁን። ፲፬ እርሱም፡ ለመቅደስ፡ ይሆናል፤ ነገር፡ ግን፡ ለሁለቱ፡ ለእስራኤል፡ ቤቶች፡ ለዕንቅፋት፡ ድንጋይና፡ ለማሰናከያ፡ ዓለት፥ በኢየሩሳሌምም፡ ለሚኖሩ፡ ለወጥመድና፡ ለአሽክላ፡ ይሆናል። ፲፭ ብዙዎችም፡ በእርሱ፡ ይሰናከላሉ፥ ይወድቁማል፥ ይሰበሩማል፥ ይጠመዱማል፥ ይያዙማል።

፲፮ ምስክሩን፡ እሰር፤ በደቀ፡ መዛሙርቶቼም፡ መካከል፡ ሕጉን፡ አትም። ፲፯ ከያዕቆብም፡ ቤት፡ ፊቱን፡ የመለሰውን፡ እግዚአብሔርን፡ እጠብቃለሁ፥ እተማመንበትማለሁ። ፲፰ እነሆ፥ እኔና፡ እግዚአብሔር፡ የሰጠኝ፡ ልጆች፡ ለእስራኤል፡ በጽዮን፡ ተራራ፡ ከሚኖረው፡ ከሠራዊት፡ ጌታ፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ምልክትና፡ ተአምራት፡ ነን።

፲፱ እነርሱም፡— የሚጮኹትንና፡ ድምፃቸውን፡ ዝቅ፡ አድርገው፡ የሚናገሩትን፡ መናፍስት፡ ጠሪዎችንና፡ ጠንቋዮችን፡ ጠይቁ፡ ባሉአችሁ፡ ጊዜ፥ ሕዝቡ፡ ከአምላኩ፡ መጠየቅ፡ አይገባውምን? ወይስ፡ ለሕያዋን፡ ሲሉ፡ ሙታንን፡ ይጠይቃሉን? ፳ ወደ፡ ሕግና፡ ወደ፡ ምስክር፡ ሂዱ! እንዲህም፡ ያለውን፡ ቃል፡ በይናገሩ፡ ንጋት፡ አይበራላቸውም። ፳፩ እነርሱም፡ ተጨንቀውና፡ ተርበው፡ ያልፋሉ፤ በተራቡም፡ ጊዜ፡ ተቈጥተው፡ ንጉሣቸውንና፡ አምላካቸውን፡ ይረግማሉ፥ ወደ፡ ላይም፡ ይመለከታሉ፤ ፳፪ ወደ፡ ምድርም፡ ይመለከታሉ፥

እነሆም ፥ መከራና ፡ ጨለማ ፡ የሚያስጨንቅም ፡ ጭጋግ ፡ አለ ፤ ወደ ፡ ድቅድቅም ፡ ጨለማ ፡ ይሰ ደዳሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ነገር ፡ ግን ፡ ተጨንቃ ፡ ለነበረች ፡ ጨለማ ፡ አይሆንም ። በመጀመሪያው ፡ ዘመን ፡ የዛብሎንንና ፡ የንፍታሌምን ፡ ምድር ፡ አቃለለ ፤ በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ ግን ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በባሕር ፡ መንገድ ፡ ያለውን ፡ የአሕዛብን ፡ ገሊላ ፡ ያከብራል ። ፪ በጨለማ ፡ የሄደ ፡ ሕዝብ ፡ ብርሃን ፡ አየ ፤ በሞት ፡ ጥላ ፡ አገርም ፡ ለኖሩ ፡ ብርሃን ፡ ወጣላቸው ። ፫ ሕዝብን ፡ አብዝተሃል ፥ ደስታንም ፡ ጨምረህላቸዋል ፤ በመከር ፡ ደስ ፡ እንደሚላቸው ፥ ሰዎችም ፡ ምርኮን ፡ ሲካፈሉ ፡ ደስ ፡ እንደሚላቸው ፡ ፬ በፊትህ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ። በምድያም ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የሸክሙን ፡ ቀንበር ፡ የጫንቃውንም ፡ በትር ፡ የአስጨናቂውንም ፡ ዘንግ ፡ ሰብ ፭ ረሃል ። የሚረግጡ ፡ የሰልፈኞች ፡ ጫማ ፡ ሁሉ ፥ በደምም ፡ የተለወሰ ፡ ልብስ ፡ ለቃጠሎ ፡ ይሆናል ፥ እንደ ፡ እሳት ፡ ማቃጠያም ፡ ሆኖ ፡ ይቃ ፮ ጠላል ። ሕፃን ፡ ተወልዶልናልና ፥ ወንድ ፡ ልጅም ፡ ተሰጥቶናልና ፤ አለቅነትም ፡ በጫንቃው ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፤ ስሙም ፡ ድንቅ ፡ መከር ፥ ኃያል ፡ አምላክ ፥ የዘላለም ፡ አባት ፥ የሰላም ፡ ፯ አለቃ ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ። ከዛሬ ፡ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ በፍርድና ፡ በጽድቅ ፡ ያጸናውና ፡ ይደግፈው ፡ ዘንድ ፡ በዳዊት ፡ ዙፋንና ፡ በመንግሥቱ ፡ ላይ ፡ አለቅነቱ ፡ ይበዛል ፥ ለሰላሙም ፡ ፍጻሜ ፡ የለውም ። የእግዚአብሔር ፡ ቅንዓት ፡ ይህን ፡ ያደርጋል ።

፰ ጌታ ፡ በያዕቆብ ፡ ላይ ፡ ቃልን ፡ ሰደደ ፥ በእ ፱፤፲ ስራኤልም ፡ ላይ ፡ ወደቀ ። በትዕቢትና ፡ በልብ ፡ ኵራት ፡— ጡቡ ፡ ወድቆአል ፥ ነገር ፡ ግን ፡ በተወቀረ ፡ ድንጋይ ፡ እንሠራለን ፤ የሾላ ፡ ዛፎች ፡ ተቈርጠዋል ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ዝግባን ፡ እንተክባቸዋለን ፡ የሚሉ ፡ በኤፍሬምና ፡ በሰማርያ ፡ የሚ ፲፩ ኖሩ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ያውቃሉ ። ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በጽዮን ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ተቋቋሚ ፡ ፲፪ ያስነሣበታል ፥ ጠላቶቹን ፡ ሶርያውያንንም ፡ ከምሥራቅ ፥ ፍልስጥኤማውያንንም ፡ ከምዕራብ ፡ ያንቀሳቅስበታል ፤ እስራኤልንም ፡ በተከፈተ ፡ አፍ ፡ ይበሉታል ። በዚህም ፡ ሁሉ ፡ እንኳ ፡ ቍጣው ፡ አልተመለሰችም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ እጁ ፡ ገና ፡ ተዘርግታ ፡ ትኖራለች ።

፲፫ ሕዝቡ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ቀሠፋቸው ፡ አልተመለሱም ፥ የሠራዊትንም ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፲፬ አልፈለጉም ። ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ራስንና ፡ ጅራትን ፥ የሰሌኑን ፡ ቅርንጫፍና ፡ እንግጫውን ፡ በአንድ ፡ ቀን ፡ ከእስራኤል ፡ ይቆ ፲፭ ርጣል ። ሽማግሌውና ፡ ከበርቴው ፡ እርሱ ፡ ራስ ፡ ነው ፤ በሐሰትም ፡ የሚያስተምር ፡ ነቢይ ፡ ፲፮ እርሱ ፡ ጅራት ፡ ነው ። ይህን ፡ ሕዝብ ፡ የሚመሩ ፡ ያስቱአቸዋል ፤ ተመሪዎቹም ፡ ይጠፋሉ ። ፲፯ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ዝንጉና ፡ ክፉ ፡ ሠሪ ፡ ነውና ፥ አፍም ፡ ሁሉ ፡ስንፍናን ፡ ይናገራልና ፡ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ በጕልማሶቻቸው ፡ ደስ ፡ አይለውም ፥ ለድሀ ፡ አደጎቻቸውና ፡ ለመበለቶቻቸውም ፡ አይራራም ። በዚህም ፡ ሁሉ ፡ እንኳ ፡ ቍጣው ፡ አልተመለሰችም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ እጁ ፡ ገና ፡ ተዘርግታ ፡ ትኖራለች ።

፲፰ ክፋት ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ይቃጠላል ፤ ኵርንችቱንና ፡ እሾሁን ፡ ይበላል ፤ ጭፍቅ ፡ የሆነውንም ፡ ዱር ፡ ያቃጥላል ፥ ጢሱም ፡ ተትጕልጕሎ ፡ ፲፱ እንደ ፡ ዓምድ ፡ ይወጣል ። በሠራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ ምድር ፡ ተቃጥላለች ፤ ሕዝቡም ፡ እሳት ፡ እንደሚበላው ፡ እንጨት ፡ ሆኖአል ፤ ሰውም ፡ ለወንድሙ ፡ አይራራም ። ፳ ሰው ፡ በቀኙ ፡ በኩል ፡ ይነቅላል ፡ ይራብማል ፤ በግራም ፡ በኩል ፡ ይበላል ፡ አይጠግብምም ፤ እያ ፳፩ ንዳንዱም ፡ የክንዱን ፡ ሥጋ ፡ ይበላል ፤ ምናሴ ፡ ኤፍሬምን ፡ ኤፍሬምም ፡ ምናሴን ፡ ይበላል ፤ እነርሱ ፡ በአንድነት ፡ የይሁዳ ፡ ጠላቶች ፡ ይሆናሉ ። በዚህም ፡ ሁሉ ፡ እንኳ ፡ ቍጣው ፡ አልተመለሰችም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ እጁ ፡ ገና ፡ ተዘርግታ ፡ ትኖራለች ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፤፪ መበለቶችም ፡ ቅሚያቸው ፡ እንዲሆኑ ፥ ድሀ ፡ አደጎችንም ፡ ብዝበዛቸው ፡ እንዲያደርጉ ፥ የድሀውን ፡ ፍርድ ፡ ያጣምሙ ፡ ዘንድ ፥ የችግረኛውንም ፡ ሕዝቤን ፡ ፍርድ ፡ ያጐድሉ ፡ ዘንድ ፡ የግፍን ፡ ትእዛዛት ፡ ለሚያዝዙ ፥ ክፋንም ፡ ፫ ጽሕፈት ፡ ለሚጽፉ ፡ ወዮላቸው ! በተጐበኛችሁበት ፡ ቀን ፥ መከራም ፡ ከሩቅ ፡ በሚመጣበት ፡ ዘመን ፡ ምን ፡ ታደርጉ ፡ ይሆን ? ለረድኤትስ ፡ ወደ ፡ ማን ፡ ትሸሻላችሁ ? ክብራችሁንስ ፡ ፬ ወዴት ፡ ትተዉታላችሁ ? ከእስረኞች ፡ በታች ፡ ይጐነበሳሉ ፥ ከተገደሉትም ፡ በታች ፡ ይወድቃሉ ። በዚህም ፡ ሁሉ ፡ እንኳ ፡ ቍጣው ፡ አልተመለሰችም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ እጁ ፡ ገና ፡ ተዘርግታ ፡ ትኖራለች ።

፭ ለቍጣዬ ፡ በትር ፡ ለሆነ ፥ የመዓቴም ፡ ጨን ፮ ገር ፡ በእጁ ፡ ላለ ፡ ለአሦር ፡ ወዮለት ! እርሱንም ፡ በዝንጉ ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ እልካለሁ ፥ ምርኮውንና ፡ ብዝበዛውንም ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ አደባባይም ፡ ጭቃ ፡ የተረገጡ ፡ ያደርጋቸው ፡ ዘንድ ፡ በምቄጣቸው ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ፯ አዝዘዋለሁ ። እርሱ ፡ እንዲሁ ፡ አያስብም ፥ በልቡም ፡ እንዲህ ፡ አይመስለውም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ማጥፋት ፥ ጥቂት ፡ ያይደሉትንም ፡ አሕዛብን ፡ ፰ መቍረጥ ፡ በልቡ ፡ አለ ። እንዲህ ፡ ይላል ፡— መሳፍንቴ ፡ ሁሉ ፡ ነገሥታት ፡ አይደሉምን ? ፱ ካልኖ ፡ እንደ ፡ ከርከሚሽ ፡ አይደለችምን ? ሐማትስ ፡ እንደ ፡ አርፋድ ፡ አይደለችምን ? ሰማ ፲ ርያስ ፡ እንደ ፡ ደማስቆ ፡ አይደለችምን ? የተቀረጹ ፡ ምስሎቻቸው ፡ ከኢየሩሳሌምና ፡ ከሰማርያ ፡ ምስሎች ፡ የበለጡትን ፡ የጣዖቶችን ፡ መን

፲፩ ግሥታት ፡ እጄ ፡ እንዳገኘች ፥ በሰማርያና ፡ በጣዖቶችዋም ፡ እንዳደረግሁ ፥ እንዲሁስ ፡ በኢየሩሳሌምና ፡ በጣዖቶችዋ ፡ አላደርግምን ?

፲፪ ስለዚህ ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ፤ ጌታ ፡ ሥራውን ፡ ሁሉ ፡ በጽዮን ፡ ተራራና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ የአሦርን ፡ ንጉሥ ፡ የኩሩ ፡ ልብ ፡ ፍሬን ፡ የዓይኑንም ፡ ከፍታ ፡ ትምክሕት ፡ ይጐበኛል ። ፲፫ እርሱ ፡ እንዲህ ፡ ብሎአልና ፡— አስተዋይ ፡ ነኝና ፡ በእጄ ፡ ኃይልና ፡ በጥበቤ ፡ አደረግሁት ፤ የአሕዛብን ፡ ድንበሮች ፡ አራቅሁ ፥ ሀብታቸውንም ፡ ዘረፍሁ ፥ እንደ ፡ ጀግናም ፡ ሆኜ ፡ በምድር ፡ የተቀመጡትን ፡ አዋረድሁ ፤ ፲፬ እጄም ፡ የአሕዛብን ፡ ኃይል ፡ እንደ ፡ ወፍ ፡ ቤት ፡ አገኘች ፤ የተተወም ፡ እንቍላል ፡ እንደሚሰበሰብ ፡ እንዲሁ ፡ እኔ ፡ ምድርን ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰብሁ ፤ ክንፉን ፡ የሚያራግብ ፡ አፉንም ፡ የሚከፍት ፡ የሚጮኽም ፡ የለም ።

፲፭ በውኑ ፡ መጥረቢያ ፡ በሚቈርጥበት ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ይመካልን ? ወይስ ፡ መጋዝ ፡ በሚስበው ፡ ላይ ፡ ይጓደዳልን ? ይህስ ፥ በትር ፡ የሚያነሣውን ፡ እንደ ፡ መነቅነቅ ፡ ዘንግም ፡ እንጨት ፡ ያይደለውን ፡ እንደ ፡ ማንሣት ፡ ያህል ፡ ነው ። ፲፮ ስለዚህም ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በወፍራሞች ፡ ላይ ፡ ክሳትን ፡ ይልካል ፤ ከክብሩም ፡ በታች ፡ ቃጠሎው ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ መቃጠል ፡ ይነድዳል ። ፲፯ የእስራኤልም ፡ ብርሃን ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ቅዱሱም ፡ እንደ ፡ ነበልባል ፡ ይሆናል ፤ እሾሁንና ፡ ኵርንችቱን ፡ በአንድ ፡ ቀን ፡ ያቃጥላል ፡ ይበላውማል ። ፲፰ ከነፍስም ፡ እስከ ፡ ሥጋ ፡ ድረስ ፡ የዱሩንና ፡ የሚያፈራውን ፡ እርሻ ፡ ክብር ፡ ይበላል ፤ ይህም ፡ የታመመ ፡ ሰው ፡ እንደሚሰለስል ፡ ይሆናል ። ፲፱ የቀሩትም ፡ የዱር ፡ ዛፎች ፡ በቍጥር ፡ ጥቂት ፡ ይሆናሉ ፥ ታናሽ ፡ ብላቴናም ፡ ይጽፋቸው ፡ ዘንድ ፡ ይችላል ።

፳ በዚያም ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ፤ የእስራኤል ፡ ቅሬታ ፡ ከያዕቆብም ፡ ቤት ፡ የዳኑት ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ በመቱአቸው ፡ ላይ ፡ አይደገፉም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በእስራኤል ፡ ቅዱስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ በእውነት ፡ ይደገፋሉ ። ፳፩ የያዕቆብም ፡ ቅሬታ ፡ ወደ ፡ ኃያል ፡ አምላክ ፡ ይመለሳሉ ። ፳፪ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ የሕዝብህ ፡ ቍጥር ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ አሸዋ ፡ ቢሆን ፡ ቅሬታው ፡ ይመለሳል ። ጽድቅ ፡ የተትረፈረፈበትም ፡ ጥፋት ፡ ተወስኖአል ። ፳፫ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ያለቀ ፡ የተቈረጠ ፡ ነገርን ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ ይፈጽማል ።

፳፬ ስለዚህ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በጽዮን ፡ የምትኖር ፡ ሕዝቤ ፡ ሆይ ፥ አሦር ፡ በበትር ፡ ቢመታህ ፥ ግብጽም ፡ እንዳደረገ ፡ ዘንጉን ፡ ቢያነሣብህ ፡ አትፍራው ። ፳፭ ቍጣዬ ፡ እስኪፈጸም ፡ መዓቴም ፡ እስኪያጠፋቸው ፡ ድረስ ፡ ጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ቀርቶአልና ። ፳፮ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ምድያምን ፡ በሔሬብ ፡ ዓለት ፡ በኩል ፡ እንደ ፡ መታው ፡ ጅራፍ ፡ ያነሣበታል ፤ በትሩም ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፥ በግብጽም ፡ እንዳደረገ ፡ ያነሣዋል ። ፳፯ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሸክሙ ፡ ከጫንቃህ ፡ ቀንበሩም ፡ ከአንገትህ ፡ ላይ ፡ ይወርዳል ፤ ቀንበሩም ፡ ከውፍረት ፡ የተነሣ ፡ ይሰበራል ።

፳፰ ወደ ፡ አንጋይ ፡ መጥቶአል ፤ በመጌዶን ፡ በኩል ፡ አልፎአል ፤ በማክማስ ፡ ውስጥ ፡ ዕቃውን ፡ አኑሮአል ፤ ፳፱ በመተላለፊያ ፡ አልፎአል ፤ በጌባ ፡ ማደሪያው ፡ ነው ፤ ራማ ፡ ደንግጣለች ፤ የሳኦል ፡ ጊብዓ ፡ ኰብልላለች ። ፴ አንቺ ፡ የጋሊም ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ በታላቅ ፡ ድምፅሽ ፡ ጩኺ ፤ ላይሳ ፡ ሆይ ፥ እድምጪ ፤ ዓናቶት ፡ ሆይ ፥ መልሽላት ። ፴፩ መደቤና ፡ ሸሽታለች ፤ በግቤርም ፡ የሚኖሩ ፡ ቤት ፡ ሰቦቻቸውን ፡ አሸሽተዋል ። ፴፪ ዛሬ ፡ በኖብ ፡ ይቆማል ፤ በጽዮን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ተራራ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ኮረብታ ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ ያንቀሳቅሳል ።

፴፫ እነሆ ፥ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቅርንጫፎቹን ፡ በሚያስፈራ ፡ ኃይል ፡ ይቈርጣል ፤ በቁመት ፡ የረዘሙትም ፡ ይቈረጣሉ ፥ ከፍ ፡ ያሉትም ፡ ይዋረዳሉ ። ፴፬ ጭፍቅ ፡ የሆነውንም ፡ ዱር ፡ በብረት ፡ ይቈርጣል ፥ ሊባኖስም ፡ በኃያሉ ፡ እጅ ፡ ይወድቃል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ከእሴይ ፡ ግንድ ፡ በትር ፡ ይወጣል ፥ ከሥሩም ፡ ቍጥቋጥ ፡ ያፈራል ። ፪ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፥ የጥበብና ፡ የማስተዋል ፡ መንፈስ ፥ የምክርና ፡ የኃይል ፡ መንፈስ ፥ የእውቀትና ፡ እግዚአብሔርን ፡ የመፍራት ፡ መንፈስ ፡ ያርፍበታል ። ፫ እግዚአብሔርን ፡ በመፍራት ፡ ደስታውን ፡ ያያል ። ዓይኑም ፡ እንደምታይ ፡ አይፈርድም ፥ ጆሮውም ፡ እንደምትሰማ ፡ አይበይንም ፤ ፬ ነገር ፡ ግን ፡ ለድሆች ፡ በጽድቅ ፡ ይፈርዳል ፥ ለምድርም ፡ የዋሆች ፡ በቅንነት ፡ ይበይናል ፤ በአፉም ፡ በትር ፡ ምድርን ፡ ይመታል ፥ በከንፈሩም ፡ እስትንፋስ ፡ ክፉዎችን ፡ ይገድላል ። ፭ የወገቡ ፡ መታጠቂያ ፡ ጽድቅ ፥ የጎኑም ፡ መቀነት ፡ ታማኝነት ፡ ይሆናል ።

፮ ተኵላ ፡ ከበግ ፡ ጠቦት ፡ ጋር ፡ ይቀመጣል ፥ ነብርም ፡ ከፍየል ፡ ጠቦት ፡ ጋር ፡ ይተኛል ፤ ጥጃና ፡ የአንበሳ ፡ ደቦል ፡ ፍሪዳም ፡ በአንድነት ፡ ያርፋሉ ፤ ታናሽም ፡ ልጅ ፡ ይመራቸዋል ። ፯ ላምና ፡ ድብ ፡ አብረው ፡ ይሰማራሉ ፥ ግልገሎቻቸውም ፡ በአንድነት ፡ ያርፋሉ ፤ አንበሳም ፡ እንደ ፡ በሬ ፡ ገለባ ፡ ይበላል ። ፰ የሚጠባውም ፡ ሕፃን ፡ በእባብ ፡ ጕድጓድ ፡ ላይ ፡ ይጫወታል ፥ ጡት ፡ የጣለውም ፡ ሕፃን ፡ በእፉኝት ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ ይጭናል ። ፱ በተቀደሰው ፡ ተራራዬ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አይጐዱም ፡ አያጠፉምም ፤ ውኃ ፡ ባሕርን ፡ እንደሚከድን ፡ ምድር ፡ እግዚአብሔርን ፡ በማወቅ ፡ ትሞላለችና ።

፲ በዚያም ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ፤ ለእሴ

ዘብ፡ምልክት፡ሊሆን፡የቆመውን፡የእሴይን፡
ሥር፡አሕዛብ፡ይፈልጉታል፤ ማረፊያውም፡
የተከበረ፡ይሆናል።
፲፩ በዚያም፡ቀን፡እንዲህ፡ይሆናል፤የቀረውን፡
የሕዝቡን፡ቅሬታ፡ከአሦርና፡ከግብጽ፥ከጳት
ሮስና፡ከኢትዮጵያ፥ከኤላምና፡ከሰናዖር፡
ከሐማትም፥ከባሕርም፡ደሴቶች፡ይመልስ፡
ዘንድ፡ጌታ፡እንደ፡ገና፡እጁን፡ይገልጣል።
፲፪ ለአሕዛብም፡ምልክትን፡ያቆማል፥ከእስራኤ
ልም፡የተጣሉትን፡ይሰበስባል፥ከይሁዳም፡የተ
በተኑትን፡ከአራቱ፡የምድር፡ማዕዘኖች፡ያከ
፲፫ ማቻል። የኤፍሬምም፡ምቀኝነት፡ይርቃል፥
ይሁዳንም፡የሚያስጨንቁ፡ይጠፋሉ፤ኤፍ
ሬምም፡በይሁዳ፡አይቀናም፥ይሁዳም፡ኤፍ
፲፬ ሬምን፡አያስጨንቅም። በምዕራብም፡በኩል፡
በፍልስጥኤማውያን፡ጫንቃ፡ላይ፡እየበረሩ፡
ይወርዳሉ፥የምሥራቅንም፡ልጆች፡በአንድ
ነት፡ይበዘብዛሉ፤በኤዶምያስና፡በሞዓብም፡
ላይ፡እጃቸውን፡ይዘረጋሉ፥የአሞንም፡ልጆች፡
፲፭ ለእነርሱ፡ይታዘዛሉ። እግዚአብሔርም፡የግ
ብጽን፡ባሕር፡ያጠፋል፤በትኩሱም፡ነፋስ፡
እጁን፡በወንዙ፡ላይ፡ያነሣል፥ሰባት፡ፈሳ
ሾችንም፡አድርጎ፡ይመታዋል፥ሰዎችንም፡
፲፮ በጫማቸው፡እንዲሻገሩ፡ያደርጋቸዋል። ከግ
ብጽም፡በወጣ፡ጊዜ፡ለእስራኤል፡እንደ፡ነበረ፥
ለቀረው፡ለሕዝቡ፡ቅሬታ፡ከአሦር፡ጐዳና፡
ይሆናል።

## ምዕራፍ፡፲፪።

፩ በዚያም፡ቀን፡— አቤቱ፥ተቈጥተኸኛልና፥
ቍጣህንም፡ከእኔ፡መልሰሃልና፥አጽናንት
፪ ኸኛልምና፡አመሰግንሃለሁ። እነሆ፥አም
ላክ፡መድኃኒቴ፡ነው፤ጌታ፡እግዚአብሔር፡
ኃይሌና፡ዝማሬዬ፡ነውና፥መድኃኒቴም፡ሆኖ
አልና፡በእርሱ፡ታምኜ፡አልፈራም፡ትላለህ።
፫ ውኃውንም፡ከመድኃኒት፡ምንጮች፡በደስታ፡
፬ ትቀዳላችሁ። በዚያም፡ቀን፡እንዲህ፡ትላ
ላችሁ፡— እግዚአብሔርን፡አመስግኑ፥ስሙ
ንም፡ጥሩ፤በአሕዛብ፡መካከል፡ሥራውን፡
አስታውቁ፤ስሙ፡ከፍ፡ያለ፡እንደ፡ሆነ፡
፭ ተናገሩ። ታላቅ፡ሥራ፡ሠርቶአልና፡ለእግ
ዚአብሔር፡ተቀኙ፤ይህንም፡በምድር፡ሁሉ፡
፮ ላይ፡አስታውቁ። አንቺ፡በጽዮን፡የምትኖሪ፡
ሆይ፥የእስራኤል፡ቅዱስ፡በመካከልሽ፡ከፍ፡
ከፍ፡ብሎአልና፡ደስ፡ይበልሽ፡እልልም፡
በዪ።

## ምዕራፍ፡፲፫።

፩ የአሞጽ፡ልጅ፡ኢሳይያስ፡ያየው፡ስለ፡
ባቢሎን፡የተነገረ፡ሸክም።
፪ ምድረ፡በዳ፡በሆነ፡ተራራ፡ላይ፡ምልክ
ትን፡አቁሙ፥ድምፅንም፡ከፍ፡አድርጉ
ባቸው፤በአለቆችም፡ደጆች፡እንዲገቡ፡
፫ በእጅ፡ጥቀሱ። ቍጣዬን፡ይፈጽሙ፡ዘንድ፡
ቅዱሳኔን፡አዝዣለሁ፥እኔ፡ኃያላኔንና፡በታ
ላቅነቴ፡ደስ፡የሚላቸውን፡ጠርቻለሁ።
፬ በተራሮች፡ላይ፡እንደ፡ታላቅ፡ሕዝብ፡ድምፅ፡
የሆነ፡የብዙ፡ሰው፡ድምፅ፡አለ። የተከማ
ቹት፡የአሕዛብ፡መንግሥታት፡የውካታ፡
ጫጫታ፡አለ። የሠራዊት፡ጌታ፡እግዚአብ
ሔር፡ሠራዊትን፡ለሰልፍ፡አሰልፎአል።
፭ እግዚአብሔርና፡የቍጣው፡የጦር፡ዕቃ፡ምድ
ርን፡ሁሉ፡ያጠፉአት፡ዘንድ፡ከሩቅ፡አገር፡
ከሰማይ፡ዳርቻ፡ይመጣሉ።
፮ የእግዚአብሔር፡ቀን፡ቀርቦአልና፥አል
ቅሱ፤ሁሉን፡ከሚችል፡አምላክ፡ዘንድ፡እን
፯ ደሚመጣ፡ጥፋት፡ይመጣል። ስለዚህ፡እጅ፡
ሁሉ፡ትዝላለች፥የሰውም፡ሁሉ፡ልብ፡ይቀ
፰ ልጣል። ይደነግጣሉ፤ምጥና፡ሕማም፡ይይዟ
ቸዋል፥እንደምትወልድ፡ሴትም፡ያምጣሉ፤
አንዱም፡በሌላው፡ይደነቃል፥ፊታቸውም፡
፱ የነበልባል፡ፊት፡ነው። እነሆ፥ምድሪቱን፡
በድማ፡ሊያደርግ፥ኃጢአተኞችዋንም፡ከእ
ርስዋ፡ዘንድ፡ሊያጠፋ፡ጨካኝ፡ሆኖ፡በመዓ
ትና፡በጽኑ፡ቍጣ፡ተሞልቶ፡የእግዚአብ
፲ ሔር፡ቀን፡ይመጣል። የሰማይም፡ከዋክብ
ትና፡ሠራዊቱ፡ብርሃናቸውን፡አይሰጡም፥
ፀሐይም፡በወጣች፡ጊዜ፡ትጨልማለች፥ጨረ
፲፩ ቃም፡በብርሃኑ፡አያበራም። ዓለሙን፡ስለ፡
ክፋታቸው፡ክፉዎቹንም፡ስለ፡በደላቸው፡
እቀጣለሁ፤የትዕቢተኞችንም፡ኵራት፡እሽራ
ለሁ፥የጨካኞቹንም፡ኵራት፡አዋርዳለሁ።
፲፪ የቀሩትም፡ከጥሩ፡ወርቅ፡ይልቅ፡የከበሩ፡
ይሆናሉ፥ሰውም፡ከኦፊር፡ወርቅ፡ይልቅ፡
፲፫ የከበረ፡ይሆናል። ስለዚህ፡በሠራዊት፡ጌታ፡
በእግዚአብሔር፡መዓት፡በጽኑ፡ቍጣ፡ቀንም፡
ሰማያትን፡አንቀጠቅጣለሁ፥ምድርም፡ከስፍ
፲፬ ራዋ፡ትናወጣለች። እንደ፡ተበረረም፡ሚዳቋ፥
ማንም፡እንደማይሰበስበው፡እንደ፡በግ፡
መንጋ፥ሰው፡ሁሉ፡ወደ፡ወገኑ፡ይመለሳል፥
፲፭ ሁሉም፡ወደ፡አገሩ፡ይሸሻል። የተገኘ፡ሁሉ፡
የተወጋ፡ይሆናል፥የተያዘም፡ሁሉ፡በሰይፍ፡
፲፮ ይወድቃል። ሕፃናቶቻቸውም፡በፊታቸው፡
ይጨፈጨፋሉ፥ቤቶቻቸውም፡ይበዘበዛሉ፥
ሚስቶቻቸውም፡ይነወራሉ።
፲፯ እነሆ፥ብር፡የማይሹትን፥ወርቅም፡የማ
ያምራቸውን፡ሜዶናውያንን፡በላያቸው፡አስ
፲፰ ነሣለሁ። ፍላጾቻቸውም፡ጐበዞችን፡ይጨፈ
ጭፋሉ፥የማኅፀንንም፡ፍሬ፡አይምሩም፥
፲፱ ዓይኖቻቸውም፡ለሕፃናት፡አይራሩም። እግ
ዚአብሔርም፡ሰዶምንና፡ገሞራን፡በፈረሰ፡
ጊዜ፡እንደ፡ነበረው፥የመንግሥታት፡ክብር፡
የከለዳውያንም፡ትዕቢት፡ጌጥ፡ባቢሎን፡እን
፳ ዲሁ፡ትሆናለች። ለዘላለም፡የሚቀመጥባት፡
አይገኝም፥ከትውልድም፡እስከ፡ትውልድ፡
ድረስ፡ሰው፡አይኖርባትም፤ዓረባውያንም፡
ድንኳንን፡በዚያ፡አይተክሉም፥እረኞችም፡
፳፩ መንጎቻቸውን፡በዚያ፡አያሳርፉም። በዚ

ያም ፡ የምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊት ፡ ያርፋሉ ÷ ጉጉ
ቶችም ፡ በቤቶቻቸው ፡ ይሞላሉ ፤ ሰጎኖችም ፡
በዚያ ፡ ይኖራሉ ÷ በዚያም ፡ አጋንንት ፡ ይዘፍ
፳፪ ናሉ ። ተኵላዎችም ፡ በግንቦቻቸው ÷ ቀበሮ
ችም ፡ በሚያማምሩ ፡ አዳራሾቻቸው ፡ ይጮ
ኻሉ ፤ ጊዜዋም ፡ ለመምጣት ፡ ቀርቦአል ፡ ቀን
ዋም ፡ አይዘገይም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ ያዕቆብን ፡ ይምረዋል ÷
እስራኤልንም ፡ ደግሞ ፡ ይመርጠዋል ÷ በአገ
ራቸውም ፡ ያኖራቸዋል ፤ መጻተኛም ፡ ከእርሱ ፡
ጋር ፡ ይተባበራል ÷ ከያዕቆብም ፡ ቤት ፡ ጋር ፡
፪ ይጣበቃል ። አሕዛብም ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ስፍራ
ቸው ፡ ያመጡአቸዋል ÷ የእስራኤልም ፡ ቤት ፡
በእግዚአብሔር ፡ ምድር ፡ እንደ ፡ ሎሌዎችና ፡
እንደ ፡ ገረዶች ፡ አድርገው ፡ ይገዙአቸዋል ፤
የማረኩአቸውን ፡ ይማርካሉ ÷ አስጨናቂዎች
ንም ፡ ይገዛሉ ።

፫ በዚያም ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ፤ እግዚአ
ብሔር ፡ ከኀዘንህና ፡ ከመከራህ ፡ ከተገዛህለትም ፡
፬ ከጽኑ ፡ ባርነት ፡ ያሳርፍሃል ። ይህንም ፡ ምሳሌ ፡
በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ላይ ፡ ታነሣለህ ፡ እንዲህም ፡
ትላለህ ፦ አስጨናቂ ፡ እንዴት ፡ ዐረፈ ! አስ
፭፡፮ ገባሪም ፡ እንዴት ፡ ጸጥ ፡ አለ ! አሕዛብንም ፡
በመዓትና ፡ በማያቋርጥ ፡ መምታት ፡ የመታ
ውን ÷ አሕዛብንም ፡ በልተከለከለ ፡ መከራ ፡
በቍጣው ፡ የገዛውን ፡ የኀጥአንን ፡ በትር ፡ የአ
ለቆችንም ፡ ዘንግ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰብሮአል ።
፯ ምድርም ፡ ሁሉ ፡ ዐርፋ ፡ በጸጥታ ፡ ተቀምጣ
፰ ለች ፡ እልልም ፡ ብላለች ። ጥድና ፡ የሊባኖስ ፡
ዝግባ ፦ አንተ ፡ ከተዋረድህ ፡ ጀምሮ ፡ ማንም ፡
ይቈርጠን ፡ ዘንድ ፡ አልወጣብንም ፡ ብለው ፡
፱ በአንተ ፡ ደስ ፡ አላቸው ። ሲኦል ፡ በመምጣትህ ፡
ልትገናኝህ ፡ በታች ፡ ታወከች ፤ የሞቱትንም ÷
የምድርን ፡ ታላላቆች ፡ ሁሉ ÷ ለአንተ ፡ አንቀሳ
ቀሰች ÷ የአሕዛብንም ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ ከዙ
፲ ፋኖቻቸው ፡ አስነሣች ። እነዚህ ፡ ሁሉ ፦
አንተ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ እኛ ፡ ደክመሃልን ? እኛ
፲፩ ንስ ፡ መስለሃልን ? ጌጥህና ፡ የበገናህ ፡ ድምፅ ፡
ወደ ፡ ሲኦል ፡ ወረደ ፤ በበታችህም ፡ ብል ፡ ተነ
ጥፎአል ÷ ትልም ፡ መደረቢያህ ፡ ሆኖአል ፡
ብለው ፡ ይመልሱልሃል ።

፲፪ አንተ ፡ የንጋት ፡ ልጅ ፡ አጥቢያ ፡ ኮከብ ፡ ሆይ ÷
እንዴት ፡ ከሰማይ ፡ ወደቅህ ! አሕዛብንም ፡ ያዋ
ረድህ ፡ አንተ ፡ ሆይ ÷ እንዴት ፡ እስከ ፡ ምድር ፡
፲፫ ድረስ ፡ ተቈረጥህ ! አንተም ፡ በልብህ ፦ ወደ ፡
ሰማይ ፡ ዐርጋለሁ ÷ ዙፋኔንም ፡ ከእግዚአብ
ሔር ፡ ከዋክብት ፡ በላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርጋለሁ ÷
በሰሜንም ፡ ዳርቻ ፡ በመሰብሰቢያ ፡ ተራራ ፡
፲፬ ላይ ፡ እቀመጣለሁ ፤ ከዳመናዎች ፡ ከፍታ ፡
በላይ ፡ ዐርጋለሁ ÷ በልዑልም ፡ እመሰላለሁ ፡
፲፭ አልህ ። ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ወደ ፡ ጕድ
፲፮ ጓዱም ፡ ጥልቅ ፡ ትወርዳለህ ። የሚያዩህ ፡ ይመ
ለከቱሃልና ፦ በውኑ ፡ ምድርን ፡ ያንቀጠቀጠ ÷
፲፯ መንግሥታትንም ፡ ያናወጠ ÷ ዓለሙን ፡ ባድማ ፡
ያደረገ ÷ ከተሞችንም ፡ ያፈረሰ ÷ ምርኮኞቹ
ንም ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ ያልሰደደ ፡ ሰው ፡ ይህ ፡
፲፰ ነውን ? ብለው ፡ ያስተውሉሃል ። የአሕዛብ ፡
ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ በየቤታቸው ፡ በክብር ፡ አን
፲፱ ቀላፍተዋል ። አንተ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ተጠላ ፡
ቅርንጫፍ ፡ ከመቃብርህ ፡ ተጥለሃል ፤ በሰይ
ፍም ፡ የተወጉት ÷ ተገድለውም ፡ ወደ ፡ ጕድ
ጓዱ ፡ ድንጋዮች ፡ የወረዱት ፡ ከድነውሃል ፤
፳ እንደ ፡ ተረገጠም ፡ ሬሳ ፡ ሆነሃል ። ምድርህን ፡
አጥፍተሃልና ÷ ሕዝብህንም ፡ ገድለሃልና ፡ ከእ
ነርሱ ፡ ጋር ፡ በመቃብር ፡ በአንድነት ፡ አትሆ
ንም ፤ የክፉዎች ፡ ዘር ፡ ለዘላለም ፡ የተጠራ ፡
፳፩ አይሆንም ። እንዳይነሡም ÷ ምድርንም ፡ እን
ዳይወርሱ ÷ የዓለሙንም ፡ ፊት ፡ በከተሞች ፡
እንዳይሞሉ ፡ ስለ ፡ አባቶቻቸው ፡ በደል ፡ ለል
፳፪ ጆቹ ፡ ሞትን ፡ አዘጋጁላቸው ። በእነርሱ ፡ ላይ ፡
እነሣለሁ ፡ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፤ ከባቢሎን ፡ ስምንና ፡ ቅሬታን ÷
ዘርንና ፡ ትውልድንም ፡ እቈርጣለሁ ፡ ይላል ፡
፳፫ እግዚአብሔር ። የጃርት ፡ መኖርያ ፡ የውኃም ፡
መቋሚያ ፡ አደርጋታለሁ ፤ በጥፋትም ፡ መጥረ
ጊያ ፡ እጠርጋታለሁ ፡ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ።

፳፬ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ብሎ ፡ ምሎአል ፦ እንደ ፡ ተናገርሁ ፡ በእርግጥ ፡
ይሆናል ÷ እንደ ፡ አሰብሁም ፡ እንዲሁ ፡ ይቆ
፳፭ ማል ። አሦርን ፡ በምድሬ ፡ ላይ ፡ እሰብረዋለሁ ÷
በተራራዬም ፡ ላይ ፡ እረግጠዋለሁ ፤ ቀንበሩም ፡
ከእነርሱ ፡ ላይ ፡ ይነሣል ÷ ሸክሙም ፡ ከጫን
፳፮ ቃቸው ፡ ላይ ፡ ይወገዳል ። በምድር ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያሰበው ፡ አሳብ ፡ ይህ ፡
ነው ÷ በአሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የተዘረጋች ፡
፳፯ እጅ ፡ ይህች ፡ ናት ። የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ይህን ፡ አስቦአል ፤ የሚያስጥለውስ ፡
ማን ፡ ነው ? እጁም ፡ ተዘርግታለች ፤ የሚመ
ልሳትስ ፡ ማን ፡ ነው ?

፳፰ ንጉሡ ፡ አካዝ ፡ በሞተበት ፡ ዓመት ፡ ይህ ፡
ሸክም ፡ ሆነ ።

፳፱ ፍልስጥኤም ፡ ሆይ ÷ ከእባቡ ፡ ሥር ፡ እፉ
ኝት ፡ ይወጣልና ÷ ፍሬውም ፡ የሚበርርና ፡
እሳት ፡ የሚመስል ፡ እባብ ፡ ይሆናልና ፡ የመ
ታሽ ፡ በትር ፡ ስለ ፡ ተሰበረ ፡ ሁላችሁም ፡ ደስ ፡
፴ አይበላችሁ ። የድሆችም ፡ የበኵር ፡ ልጆች ፡
ይሰማራሉ ÷ ችግረኞችም ፡ ተዘልለው ፡ ይተ
ኛሉ ፤ ሥርህንም ፡ በራብ ፡ እገድላለሁ ÷ ቅሬ
፴፩ ታህም ፡ ይገደላል ። አንተ ፡ በር ፡ ሆይ ÷ ወዮ ፡
በል ፤ አንቺም ፡ ከተማ ፡ ሆይ ÷ ጩኺ ፤ ፍልስ
ጥኤም ፡ ሆይ ÷ ሁላችሁም ፡ ቀልጣችኋል ፤ ጢስ ፡
ከሰሜን ፡ ይመጣል ፡ ከጭፍራውም ፡ ተለይቶ ፡
የሚቀር ፡ የለም ።

፴፪ ለሕዝቡም ፡ መልእክተኞች ፡ ምን ፡ ብሎ ፡
መመለስ ፡ ይገባል ? እግዚአብሔር ፡ ጽዮንን ፡

እንደ ፡ መሠረተ ÷ የሕዝቡም ፡ ችግረኞች ፡ በእ
ርስዋ ፡ ውስጥ ፡ እንደሚጠጉ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ ስለ ፡ ሞዓብ ፡ የተነገረ ፡ ሸክም ።
የሞዓብ ፡ ዔር ፡ በሌሊት ፡ ፈርሶ ፡ ጠፋ ፤
ቂር ፡ የሚባልም ፡ የሞዓብ ፡ ምሽግ ፡ በሌሊት ፡
፪ ፈርሶ ፡ ጠፋ ። ወደ ፡ ባይት ፡ ወደ ፡ ዲቦንም ፡
ወደ ፡ ከረብታ ፡ መስገጃዎችም ፡ ለልቅሶ ፡ ወጥ
ተዋል ፤ ሞዓብ ፡ በናባውና ፡ በሜድባ ፡ ላይ ፡
ታለቅሳለች ፤ ራሳቸው ፡ ሁሉ ፡ ተነጭቶአል ÷
፫ ጢማቸውም ፡ ሁሉ ፡ ተላጭቶአል ። በየመን
ገዳቸውም ፡ በማቅ ፡ ታጥቀዋል ፤ በየሰገነቶ
ቻቸውና ፡ በየአደባባዮቻቸው ፡ እንባ ፡ እጅግ ፡
፬ እያፈሰሱ ፡ ሁሉም ፡ አልቅሰዋል ። ሐሴቦንና ፡
ኤልያሊ ፡ ጮኹ ፤ ድምፃቸው ፡ እስከ ፡ ያህጽ ፡
ድረስ ፡ ይሰማል ፤ ስለዚህ ፡ የሞዓብ ፡ ሰልፈ
ኞች ፡ ጮኹ ፤ ነፍስዋ ፡ በውስጥዋ ፡ ተንቀጠ
፭ ቀጠች ። ልቤ ፡ ስለ ፡ ሞዓብ ፡ ጮኸ ፤ ከእር
ስዋ ፡ የሚሸሹ ፡ ወደ ፡ ዞዓር ፡ ወደ ፡ ዔግላት ፡
ሺሊሺያ ፡ ኰበለሉ ፤ በሉሒት ፡ ዓቀበት ፡ ላይ ፡
እያለቀሱ ፡ ይወጣሉ ÷ በሖሮናይምም ፡ መን
፮ ገድ ፡ የዋይታ ፡ ጩኸት ፡ ያነሣሉ ። የኔምሬም ፡
ውኆች ፡ ይደርቃሉ ፤ ሣሩም ፡ ደርቋል ÷ ለጋ
ውም ፡ ጠውልጓል ÷ ልምላሜውም ፡ ሁሉ ፡
፯ የለም ። ስለዚህ ፡ የሰበሰቡትን ፡ ሀብትና ፡
መዝገባቸውን ፡ ወደ ፡ አኻያ ፡ ዛፍ ፡ ወንዝ ፡
፰ ማዶ ፡ ይወስዱታል ። ጩኸት ፡ የሞዓብን ፡
ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ ዞረ ፤ ልቅሶዋም ፡ ወደ ፡ ኤግላይ
፱ ምና ፡ ወደ ፡ ብኤርኤሊም ፡ ደረሰ ። የዲሞንም ፡
ውኃ ፡ ደም ፡ ተሞልታለች ፤ በዲሞንም ፡ ላይ ፡
ሥቃይን ፡ እጨምራለሁ ÷ ከሞዓባውያንም ፡
በሚያመልጡ ÷ ከምድርም ፡ በሚቀሩ ፡ ላይ ፡
አንበሳን ፡ አመጣለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ በምድር ፡ ላይ ፡ ለሠለጠነው ፡ አለቃ ፡ የበግ ፡
ጠቦቶችን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ካለችው ፡ ከሴላ ፡
ወደ ፡ ጽዮን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ተራራ ፡ ስደዱ ።
፪ እንደሚበርር ፡ ወፍ ፡ እንደ ፡ ተበተኑም ፡ ጫጩ
ቶች ፡ እንዲሁ ፡ የሞዓብ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ በአ
ርኖን ፡ መሻገሪያዎች ፡ ይሆናሉ ።
፫ ምክርን ፡ ምከሪ ÷ ፍርድን ፡ አድርጊ ÷ በቀ
ትር ፡ ጊዜ ፡ ጥላሽን ፡ እንደ ፡ ሌሊት ፡ አድርጊ ፤
የተሰደዱትን ፡ ሸሽጊ ÷ የሸሹትን ፡ አትግለጪ ።
፬ ከሞዓብ ፡ የተሰደዱት ፡ ከአንቺ ፡ ጋር ፡ ይቀመጡ ፤
ከሚያጠፋቸው ፡ ፊት ፡ መጋረጃ ፡ ሁኛቸው ።
የሚያስጨንቁ ፡ አልቀዋል ÷ ጥፋትም ፡ ቀርቶ
አል ፤ ይጨቁኑ ፡ የነበሩ ፡ ከምድር ፡ ጠፍተ
፭ ዋል ። ዙፋንም ፡ በምሕረት ፡ ይቀናል ÷ በዚ
ያም ፡ ላይ ፡ በዳዊት ፡ ድንኳን ፡ ፍርድን ፡ የሚሻ ፡
ጽድቅንም ፡ የሚያፋጥን ፡ ፈራጅ ፡ በእውነት ፡
ይቀመጣል ።
፮ ስለ ፡ ሞዓብ ፡ ትዕቢት ፡ እጅግ ፡ ስለ ፡ መታ
በዩ ÷ ስለ ፡ ኩራቱና ፡ ስለ ፡ ትዕቢቱ ፡ ስለ ፡
ቍጣውም ፡ ሰምተናል ፤ ትምክሕቱ ፡ ከንቱ ፡
፯ ነው ። ስለዚህ ፡ ሞዓብ ፡ ስለ ፡ ሞዓብ ፡ ዋይ ፡
ይላል ፤ ሁሉም ፡ ዋይ ፡ ይላል ፤ ስለ ፡ ቂርሐራሴት ፡
መሠራት ፡ በጥልቅ ፡ ኀዘን ፡ ታለቅሳላችሁ ።
፰ የሐሴቦን ፡ እርሻዎችና ፡ የሴባማ ፡ ወይን ፡ ግን
ዶች ፡ አዝነዋል ። የአሕዛብ ፡ አለቆች ፡ የሰባበ
ሩአቸው ፡ ቅርንጫፎች ፡ እስከ ፡ ኢያዜር ፡ ደር
ሰው ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወጥተው ፡ ነበር ፤
ቍጥቋጦቹም ፡ ተዘርግተው ፡ በሕርን ፡ ተሻግ
፱ ረው ፡ ነበር ። ስለዚህ ፡ በኢያዜር ፡ ልቅሶ ፡
ስለ ፡ ሴባማ ፡ ወይን ፡ ግንድ ፡ አለቅሳለሁ ፤ ሐሴ
ቦንና ፡ ኤልያሊ ፡ ሆይ ÷ በዛፍሽ ፡ ፍሬና ፡ በወ
ይንሽ ፡ መከር ፡ የጦር ፡ ጩኸት ፡ ወድቆአልና ፡
፲ በእንባዬ ፡ አረከሻለሁ ። ደስታና ፡ ሐሤትም ፡
ከፍሬያማው ፡ እርሻ ፡ ተወስዶአል ÷ በወይኑም ፡
ቦታዎች ፡ ዝማሬና ፡ እልልታ ፡ የለም ፤ በመጥ
መቂያም ፡ ወይን ፡ የሚረግጥ ፡ የለም ፤ የረጋጮ
፲፩ ቹን ፡ እልልታ ፡ አጥፍቻለሁ ። ስለዚህ ፡ ልቤ ፡
ስለ ፡ ሞዓብ ፡ አንጀቴም ፡ ስለ ፡ ቂርሔሬስ ፡ እንደ ፡
፲፪ መሰንቆ ፡ ትጮኻለች ። ሞዓብም ፡ መጥቶ ፡ በከ
ረብታ ፡ መስገጃ ፡ ላይ ፡ በደከመና ፡ ለጸሎት ፡
ወደ ፡ መቅደሱ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ አያሸንፍም ።
፲፫ እግዚአብሔር ፡ በሞዓብ ፡ ላይ ፡ በድሮ ፡ ዘመን ፡
፲፬ የተናገረው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ። አሁን ፡ ግን ፡
እግዚአብሔር ፡— በሦስት ፡ ዓመት ፡ ውስጥ ፡
እንደ ፡ ምንደኛ ፡ ዓመት ፡ የሞዓብ ፡ ክብርና ፡ የሕ
ዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ብዛት ፡ ይዋረዳል ÷ ቅሬታውም ፡
እጅግ ፡ ያነሰና ፡ የተጠቃ ፡ ይሆናል ፡ ይላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ ስለ ፡ ደማስቆ ፡ የተነገረ ፡ ሸክም ።
እነሆ ÷ ደማስቆ ፡ ከተማ ፡ ከመሆን ፡ ተቋርጣ
ለች ፤ በድማና ፡ የፍርስራሽ ፡ ክምር ፡ ትሆናለች ።
፪ ከተሞችዋ ፡ ለዘላለም ፡ የተፈቱ ፡ ይሆናሉ ፤ ለመ
ንጋ ፡ ማሰማርያ ፡ ይሆናሉ ፤ መንጎች ፡ በዚያ ፡
፫ ያርፋሉ ፡ የሚያስፈራቸውም ፡ የለም ። ምሽ
ግም ፡ ከኤፍሬም ÷ መንግሥትም ፡ ከደማስቆ ፡
ተወገደች ፤ የሶርያም ፡ ቅሬታ ፡ እንደ ፡ እስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ ክብር ፡ ይሆናል ፡ ይላል ፡ የሠራ
ዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።
፬ በዚያም ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ፤ የያዕቆብ ፡
ክብር ፡ ይደክማል ፡ የሥጋውም ፡ ውፍረት ፡
፭ ይከሳል ። አጫጅ ፡ የቆመውን ፡ እህል ፡ በእጁ ፡
ሰብስቦ ፡ ዛላውን ፡ እንደሚያጭድ ፡ ይሆናል ፤
በራፋይም ፡ ሸለቆ ፡ ቃርሚያ ፡ እንደሚለቅም ፡
፮ እንዲሁ ፡ ይሆናል ። ወይራ ፡ በተመታ ፡ ጊዜ ፡
ሁለት ፡ ወይም ፡ ሦስት ፡ ፍሬ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡
እንደሚቀር ÷ አራት ፡ ወይም ፡ አምስት ፡ በዛ
ፊቱ ፡ ጫፍ ፡ እንደሚገኝ ÷ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡
ቃርሚያ ፡ ይቀራል ፡ ይላል ፡ የእስራኤል ፡ አም
፯ ላክ ፡ እግዚአብሔር ። በዚያ ፡ ቀን ፡ ሰው ፡ ወደ ፡
ፈጣሪው ፡ ይመለከታል ÷ ዓይኖቹም ፡ ወደ ፡ እስ
፰ ራኤል ፡ ቅዱስ ፡ ያያሉ ። እጁም ፡ የሠራችውን ፡

መሠዊያ ፡ አይመለከትም ፤ ጣቶቹም ፡ ወደ ፡ አበጁአቸው ፥ ወደ ፡ ማምለኪያ ፡ ዐፀዶች ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ ፀሐይ ፡ ምስሎች ፥ አያይም ።

፱ ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ የአሞራውያንና ፡ የኤዊያውያን ፡ ከተሞች ፡ እንደ ፡ ተፈቱ ፥ እንዲሁ ፡ ከተሞችህ ፡ ይፈታሉ ፥ በድማም ፡ ይሆናሉ ። ፲ ፤ የደኅንነትህን ፡ አምላክ ፡ ረስተሃል ፥ የረድኤትህንም ፡ ጌታ ፡ አላሰብህም ፤ ስለዚህ ፡ ያማረውን ፡ ተክል ፡ ተክለሃል ፥ እንግዳንም ፡ ዘር ፡ ዘርተሃል ። ፲፩ ፤ በተከልህበት ፡ ቀን ፡ ታበቅለዋለህ ፥ በነጋውም ፡ ዘርህን ፡ እንዲያብብ ፡ ታደርገዋለህ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በኀዘንና ፡ በትካዜ ፡ ቀን ፡ መከሩ ፡ ይሸሻል ።

፲፪ ፤ እንደ ፡ ባሕር ፡ ሞገድ ፡ ድምፅ ፡ ለሚተምሙ ፡ ለወገኖች ፡ ብዛት ፥ እንደ ፡ ኃይለኛም ፡ ውኃ ፡ ጩኸት ፡ ለሚጮኹ ፡ አሕዛብ ፡ ወዮላቸው ! ፲፫ ፤ አሕዛብ ፡ እንደ ፡ ብዙ ፡ ውኃ ፡ ጩኸት ፡ ይጮኻሉ ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ ይገሥጻቸዋል ፥ እነርሱም ፡ እየሸሹ ፡ ይርቃሉ ፥ በተራራም ፡ ላይ ፡ እንዳለ ፡ እብቅ ፡ በነፋስ ፡ ፊት ፥ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ እንደሚያዘረውም ፡ ትቢያ ፡ ይበተናሉ ። ፲፬ ፤ በመሸ ፡ ጊዜ ፥ እነሆ ፥ ድንጋጤ ፡ አለ ፤ ከማለዳም ፡ በፊት ፡ አይገኙም ። የዘረፉን ፡ ሰዎች ፡ እድል ፡ ፈንታ ፥ የበዘበዙንም ፡ ዕጣ ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ ፤ በኢትዮጵያ ፡ ወንዞች ፡ ማዶ ፡ ላለች ፥ ክንፍ ፡ ፪ ፤ ያላቸው ፡ መርከቦች ፡ ላሉባት ፥ መልእክተኞችን ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡ የደንገል ፡ መርከቦችንም ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡ ለምትልክ ፡ ምድር ፡ ወዮላት ! እናንተ ፡ ፈጣኖች ፡ መልእክተኞች ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ ረጅምና ፡ ወደ ፡ ለስላሳ ፡ ሕዝብ ፥ ከመጀመሪያው ፡ አስደንጋጭ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ወገን ፥ ወደሚሰፍርና ፡ ወደሚረግጥ ፥ ወንዞችም ፡ ምድራቸውን ፡ ወደሚከፍሉት ፡ ሕዝብ ፡ ሂዱ ። ፫ ፤ በዓለም ፡ የምትኖሩ ፡ ሁሉና ፡ በምድር ፡ የምትቀመጡ ፡ ሆይ ፥ ምልክት ፡ በተራሮች ፡ ላይ ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ እዩ ፤ መለከትም ፡ በተነፋ ፡ ጊዜ ፡ ስሙ ።

፬ ፤ እግዚአብሔር ፦ በፀሐይ ፡ ጮራ ፡ እንደ ፡ ደረቅ ፡ ትኩሳት ፥ በአጨዳም ፡ ወራት ፡ እንደ ፡ ጠል ፡ ደመና ፡ ሆኜ ፡ በማደሪያዬ ፡ በጸጥታ ፡ ፭ ፤ ተቀምጬ ፡ እመለከታለሁ ፡ ብሎኛልና ። እርሱ ፡ ከመከር ፡ በፊት ፡ አበባ ፡ በረገፈ ፡ ጊዜ ፡ የወይንም ፡ ፍሬ ፡ ጨርቋ ፡ ሲይዝ ፡ የወይኑን ፡ ዘንግ ፡ በማጭድ ፡ ይቈርጣል ፥ ጫፎቹንም ፡ ይመለምላል ፡ ፮ ፤ ያስወግድማል ። በተራራ ፡ ላይ ፡ ላሉ ፡ ነጣቂዎች ፡ ወፎች ፥ ለምድርም ፡ አውሬዎች ፡ በአንድነት ፡ ይቀራሉ ፤ ነጣቂዎችም ፡ ወፎች ፡ ይበጁባቸዋል ፥ የምድርም ፡ አውሬዎች ፡ ሁሉ ፡ ፯ ፤ ይከርሙባቸዋል ። በዚያን ፡ ዘመን ፡ ለሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፥ ከረጅምና ፡ ከለስላሳ ፡ ሕዝብ ፥ ከመጀመሪያው ፡ አስደንጋጭ ፡ ከሆነ ፡ ወገን ፥ ከሚሰፍርና ፡ ከሚረግጥ ፥ ወንዞችም ፡ ምድራቸውን ፡ ከሚከፍሉት ፡ ሕዝብ ፡ ዘንድ ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ወደሚገኝበት ፡ ስፍራ ፡ ወደ ፡ ጽዮን ፡ ተራራ ፡ ይቀርባል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ ፤ ስለ ፡ ግብጽ ፡ የተነገረ ፡ ሸክም ።

እነሆ ፥ እግዚአብሔር ፡ በፈጣን ፡ ደመና ፡ እየበረረ ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ይመጣል ፤ የግብጽም ፡ ጣዖታት ፡ በፊቱ ፡ ይርዳሉ ፥ የግብጽም ፡ ልብ ፡ በውስጥዋ ፡ ይቀልጣል ። ፪ ፤ ግብጻውያንን ፡ በግብጻውያን ፡ ላይ ፡ አስነሣለሁ ፤ ወንድምም ፡ ወንድሙን ፥ ሰውም ፡ ባልንጀራውን ፥ ከተማም ፡ ከተማን ፥ መንግሥትም ፡ መንግሥትን ፡ ይወጋል ። ፫ ፤ የግብጽም ፡ መንፈስ ፡ በውስጥዋ ፡ ባዶ ፡ ይሆናል ፥ ምክራቸውንም ፡ አጠፋለሁ ፤ እነርሱም ፡ ጣዖቶቻቸውን ፡ በድግምት ፡ የሚጠነቍሉትንም ፡ መናፍስት ፡ ጠሪዎቻቸውንም ፡ ጠንቋዮቻቸውንም ፡ ይጠይቃሉ ። ፬ ፤ ግብጻውያንንም ፡ በጨካኝ ፡ ጌታ ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣለሁ ፤ ጨካኝ ፡ ንጉሥም ፡ ይገዛቸዋል ፡ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፭ ፤ ውኆችም ፡ ከባሕር ፡ ይደርቃሉ ፥ ወንዙም ፡ ፮ ፤ ያንሳል ፡ ደረቅም ፡ ይሆናል ። ወንዞቹም ፡ ይገማሉ ፥ የግብጽም ፡ መስኖች ፡ ያንሳሉ ፡ ይደርቃሉም ፤ ደንገልና ፡ ቄጠማ ፡ ይጠወልጋሉ ። ፯ ፤ በዓባይ ፡ ወንዝ ፡ ዳር ፡ ያለው ፡ መስክ ፡ በዓባይም ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ የተዘራ ፡ እርሻ ፡ ሁሉ ፡ ይደርቃል ፥ ይበተንማል ፥ አይገኝምም ። ፰ ፤ ዓሣ ፡ አጥማጆቹ ፡ ያዝናሉ ፥ በዓባይም ፡ ወንዝ ፡ መቃጥን ፡ የሚጥሉት ፡ ሁሉ ፡ ያለቅሳሉ ፥ በውኆችም ፡ ላይ ፡ መረብ ፡ የሚዘረጉት ፡ ይዝላሉ ። ፱ ፤ የተበጠረውንም ፡ የተልባ ፡ እግር ፡ የሚሠሩ ፥ ነጩንም ፡ ልብስ ፡ የሚሠሩ ፡ ሸማኔዎች ፡ ያፍራሉ ። ፲ ፤ ደገፋዎችዋም ፡ ሁሉ ፡ ይሰባበራሉ ፥ የደመወዘኞችም ፡ ነፍስ ፡ ትተክዛለች ።

፲፩ ፤ የጣኔዎስ ፡ አለቆች ፡ ፍጹም ፡ ሰነፎች ፡ ናቸው ፤ ፈርዖንን ፡ የሚመክሩ ፡ ጥበበኞች ፡ ምክራቸው ፡ ድንቍርና ፡ ሆነች ። ፈርዖንን ፦ እኛ ፡ የጥበበኞች ፡ ልጆች ፡ የቀደሙም ፡ ነገሥታት ፡ ልጆች ፡ ነን ፡ እንዴት ፡ ትሉታላችሁ ? ፲፪ ፤ አሁንሳ ፡ ጥበበኞችህ ፡ የት ፡ አሉ ? አሁን ፡ ይንገሩህ ፤ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በግብጽ ፡ ላይ ፡ ያሰበውን ፡ ይወቁ ። ፲፫ ፤ የጣኔዎስ ፡ አለቆች ፡ ሰነፎች ፡ ሆነዋል ፥ የሜምፎስም ፡ አለቆች ፡ ተሸንግለዋል ፤ የነገዶችዋ ፡ የማዕዘን ፡ ድንጋዮች ፡ የሆኑ ፡ ግብጽን ፡ አሳቱ ። ፲፬ ፤ እግዚአብሔር ፡ የጠማምነትን ፡ መንፈስ ፡ በውስጥዋ ፡ ደባልቆአል ፤ ሰካር ፡ በትፋቱ ፡ እንዲስት ፡ እንዲሁ ፡ ግብጽን ፡ በሥራዋ ፡ ሁሉ ፡ አሳቱ ። ፲፭ ፤ ራስ ፡ ወይም ፡ ጅራት ፡ የሰሌን ፡ ቅርንጫፍ ፡ ወይም ፡ እንግጫ ፡ ቢሆን ፡ ሊሠራ ፡ የሚችል ፡ ሥራ ፡ ለግብጽ ፡ አይሆንላትም ።

፲፮ ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ ግብጻውያን ፡ እንደ ፡ ሴቶች ፡ ይሆናሉ ፥ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡

በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ከሚያንቀሳቅሳት ፡ ከእጁ ፡ መን
ቀሳቀስ ፡ የተነሣ ፡ ይሸበራሉ ፡ ይፈሩማል ።
፲፯፡ የይሁዳም ፡ ምድር ፡ ግብጽን ፡ የምታስደነግጥ ፡
ትሆናለች ፤ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡
ከመከረበት ፡ ምክር ፡ የተነሣ ፡ ወሬዋን ፡ የሚ
ሰማ ፡ ሁሉ ፡ ይፈራል ።
፲፰፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ በግብጽ ፡ ምድር ፡ በከነዓን ፡
ቋንቋ ፡ የሚናገሩ ፥ በሠራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግዚ
አብሔርም ፡ የሚምሉ ፡ አምስት ፡ ከተሞች ፡
ይሆናሉ ፤ ከነዚህም ፡ አንዲቱ ፡ የጥፋት ፡ ከተማ ፡
ተብላ ፡ ትጠራለች ።
፲፱፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ በግብጽ ፡ ምድር ፡ መካከል ፡
ለእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፥ በዳርቻዋም ፡ ለእ
፳፡ ግዚአብሔር ፡ ዓምድ ፡ ይሆናል ። ይህም ፡ ለሠ
ራዊት ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በግብጽ ፡
ምድር ፡ ምልክትና ፡ ምስክር ፡ ይሆናል ፤ ከሚ
ያስጨንቁአቸው ፡ የተነሣ ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ይጮኻሉና ፥ እርሱም ፡ መድኃኒትንና ፡
፳፩፡ ኃያልን ፡ ሰድዶ ፡ ያድናቸዋልና ። በዚያም ፡
ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ በግብጽ ፡ የታወቀ ፡ ይሆ
ናል ፥ ግብጻውያንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያው
ቃሉ ፤ በመሥዋዕትና ፡ በቍርባን ፡ ያመልካሉ ፥
ለእግዚአብሔርም ፡ ስእለት ፡ ይሳላሉ ፡ ይፈጽ
፳፪፡ ሙትማል ። እግዚአብሔርም ፡ ግብጽን ፡ ይመ
ታታል ፤ ይመታታል ፡ ይፈውሳታልም ፤ ወደ ፡
እግዚአብሔርም ፡ ይመለሳሉ ፡ እርሱም ፡ ይለ
መናቸዋል ፡ ይፈውሳቸውማል ።
፳፫፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ከግብጽ ፡ ወደ ፡ አሦር ፡ መን
ገድ ፡ ይሆናል ፥ አሦራዊውም ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፥ ግብ
ጻዊውም ፡ ወደ ፡ አሦር ፡ ይገባል ፤ ግብጻውያንም ፡
ከአሦራውያን ፡ ጋር ፡ ይሰግዳሉ ።
፳፬፡፳፭፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡— ሕዝቤ ፡
ግብጽ ፥ የእጄም ፡ ሥራ ፡ አሦር ፥ ርስቴም ፡ እስ
ራኤል ፡ የተባረከ ፡ ይሁን ፡ ብሎ ፡ ይባርካቸዋልና ፡
በዚያ ፡ ቀን ፡ እስራኤል ፡ ለግብጽና ፡ ለአሦር ፡
ሦስተኛ ፡ ይሆናል ፥ በምድርም ፡ መካከል ፡ በረ
ከት ፡ ይሆናል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ሳርጎን ፡ ተርታንን ፡ በሰደደ ፡
ጊዜ ፡ እርሱም ፡ ወደ ፡ አዛጦን ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡
፪፡ አዛጦንም ፡ ወግቶ ፡ በያዛት ፡ ጊዜ ፥ በዚያ ፡
ዓመት ፡ እግዚአብሔር ፡ የአሞጽን ፡ ልጅ ፡ ኢሳ
ይያስን ፡— ሂድ ፥ ማቅህን ፡ ከወገብህ ፡ አውጣ ፡
ጫማህንም ፡ ከእግርህ ፡ አውልቅ ፡ ብሎ ፡ ተናገ
ረው ። እንዲህም ፡ አደረገ ፥ ራቁቱንም ፡ ባዶ ፡
፫፡ እግሩንም ፡ ሄደ ። እግዚአብሔርም ፡ አለ ፡—
ባሪያዬ ፡ ኢሳይያስ ፡ በግብጽና ፡ በኢትዮጵያ ፡
ላይ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ለምልክትና ፡ ለተአም
ራት ፡ ሊሆን ፡ ራቁቱንና ፡ ባዶ ፡ እግሩን ፡ እንደ ፡
፬፡ ሄደ ፥ እንዲሁ ፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ የግብጽንና ፡
የኢትዮጵያን ፡ ምርኮ ፥ ጕበዛዝቱንና ፡ ሽማግ
ሌዎቹን ፥ ራቁታቸውንና ፡ ባዶ ፡ እግራቸውን ፡
አድርጎ ፡ ገላቸውንም ፡ ገልጦ ፥ ለግብጽ ፡ ጕስ
ቍልና ፡ ይነዳቸዋል ። እነርሱም ፡ ከተስፋቸው ፡ ፭፡
ከኢትዮጵያ ፡ ከትምክሕታቸውም ፡ ከግብጽ ፡
የተነሣ ፡ ይፈራሉ ፡ ያፍሩማል ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ፮፡
በዚች ፡ በሕር ፡ ዳርቻ ፡ የሚቀመጡ ፡— እነሆ ፥
ከአሦር ፡ ንጉሥ ፡ እንድን ፡ ዘንድ ፡ ለእርዳታ ፡
ወደ ፡ እነርሱ ፡ የሸሸንበት ፡ ተስፋችን ፡ ይህ ፡
ነበረ ፤ እኛስ ፡ እንዴት ፡ እናመልጣለን ? ይላሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩፡ በባሕር ፡ አጠገብ ፡ ስላለው ፡ ስለ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
የተነገረ ፡ ሸክም ።
ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ከደቡብ ፡ እንደሚወጣ ፥ እን
ዲሁ ፡ ከሚያስፈራ ፡ አገር ፡ ከምድረ ፡ በዳ ፡ ይወ
ጣል ። ከባድ ፡ ራእይ ፡ ተነገረኝ ፤ ወንጀለኛው ፡ ፪፡
ይወነጅላል ፡ አጥፊውም ፡ ያጠፋል ። ኤላም ፡
ሆይ ፥ ውጪ ፤ ሜዶን ፡ ሆይ ፥ ከበቢ ፤ ትካዜ
ውን ፡ ሁሉ ፡ አስቀርቻለሁ ። ስለዚህ ፡ ወገቤ ፡ ፫፡
ሕመም ፡ ተሞላ ፤ እንደምትወልድ ፡ ሴት ፡ ምጥ ፡
ያዘኝ ፤ ከሕመሜ ፡ የተነሣ ፡ አልሰማም ፥ ከድን
ጋጤም ፡ የተነሣ ፡ አላይም ። ልቤ ፡ ተንበደ ፡ ፬፡
በደ ፥ ድንጋጤ ፡ አስፈራኝ ፥ ተስፋ ፡ ያደረግ
ሁትም ፡ ድንግዝግዝታ ፡ መንቀጥቀጥ ፡ ሆነብኝ ።
ማዕዱን ፡ ያዘጋጃሉ ፥ ምንጣፉንም ፡ ይዘረጋሉ ፥ ፭፡
ይበሉማል ፥ ይጠጡማል ፤ እናንተ ፡ መሳፍ
ንት ፡ ሆይ ፥ ተነሡ ፥ ጋሻውን ፡ አዘጋጁ ።
ጌታ ፡ እንዲህ ፡ ብሎኛልና ፡— ሂድ ፡ ጕበኛም ፡ ፮፡
አቁም ፥ የሚያየውንም ፡ ይናገር ። በከብት ፡ ፯፡
የሚቀመጡትን ፥ ሁለት ፡ ሁለት ፡ እየሆኑ ፡ የሚ
ሄዱት ፡ ፈረሰኞች ፥ በአህዮች ፡ የሚቀመጡ
ትንና ፡ በግመሎች ፡ የሚቀመጡትን ፡ በየ ፡
ጊዜ ፡ በጽኑ ፡ ትጋት ፡ አስተውሎ ፡ ተግቶም ፡
ያድምጥ ። ያየውም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ቀኑን ፡ ፰፡
ሁሉ ፡ ዘወትር ፡ በማማ ፡ ላይ ፡ ቆሜአለሁ ፥
ሌሊቱንም ፡ ሁሉ ፡ በመጠበቂያዬ ፡ ላይ ፡ ተተከ
ያለሁ ፤ እነሆም ፥ በፈረሶች ፡ የሚቀመጡ ፥ ፱፡
ሁለት ፡ ሁለት ፡ ሁነው ፡ የሚሄዱ ፡ ፈረሰኞች ፡
ይመጣሉ ፡ ብሎ ፡ ጮኸ ፤ እርሱም ፡ መልሶ ፡—
ባቢሎን ፡ ወደቀች ፡ ወደቀች ፥ የተቀረጹም ፡ የአ
ማልክቶችዋ ፡ ምስሎች ፡ ሁሉ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡
ተጥለው ፡ ደቀቁ ፡ አለ ። እናንተ ፡ በአውድ ፡ ፲፡
ማዬ ፡ ላይ ፡ የተወቃችሁ ፡ የአውድማዬ ፡ ልጆች ፡
ሆይ ፥ ከእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ከሠራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፡ የሰማሁትን ፡ ነገርኋችሁ ።
፲፩፡ ስለ ፡ ኤዶምያስ ፡ የተነገረ ፡ ሸክም ።
አንዱ ፡ ከሴይር ፡— ጕበኛ ፡ ሆይ ፥ ሌሊቱ ፡
ምን ፡ ያህል ፡ ነው ? ጕበኛ ፡ ሆይ ፥ ሌሊቱ ፡
ምን ፡ ያህል ፡ ነው ? ብሎ ፡ ጠራኝ ። ጕበኛ ፡ ፲፪፡
ውም ፡— ይነጋል ፡ ደግሞም ፡ ይመሻል ፤ ትጠ
ይቁ ፡ ዘንድ ፡ ብትወድዱ ፡ ጠይቁ ፤ ተመልሳች
ሁም ፡ ኑ ፡ አለ ።
፲፫፡ ስለ ፡ ዓረብ ፡ የተነገረ ፡ ሸክም ።
የድዳናውያን ፡ ነጋዴዎች ፡ ሆይ ፥ በዓረብ ፡
ዱር ፡ ውስጥ ፡ ታድራላችሁ ። በቴማን ፡ የምት ፡ ፲፬፡
ኖሩ ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ ተጠሙት ፡ ሰዎች ፡ ውኃ ፡

አምጡ ፤ እንጀራ ፡ ይዛችሁ ፡ የሸሹትን ፡ ሰዎች ፡
፲፭ ተቀበሉአቸው ። ከሰይፍ ÷ ከተመዘዘው ፡
ሰይፍ ÷ ከተለጠጠውም ፡ ቀስት ፡ ከጽኑም ፡
፲፮ ሰልፍ ፡ ሸሽተዋልና ። ጌታ ፡ እንዲህ ፡ ብሎኛ
ልና ፡— እንደ ፡ ምንደኛ ፡ ዓመት ፡ በአንድ ፡
ዓመት ፡ ውስጥ ፡ የቄዳር ፡ ክብር ፡ ሁሉ ፡ ይጠ
፲፯ ፋል ፤ ከቀስተኞች ፡ ቍጥር ፡ የቀሩት ÷ የቄዳር ፡
ልጆች ፡ ኃያላን ÷ ያንሳሉ ፤ የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናግሮአልና ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ ስለ ፡ ራእይ ፡ ሸለቆ ፡ የተነገረ ፡ ሸክም ።
እናንተ ፡ ሁላችሁ ፡ ወደ ፡ ሰገነት ፡ መውጣታ
፪ ችሁ ፡ ምን ፡ ሆናችኋል ? ጩኸትና ፡ ፍጅት ፡
የተሞላብሽ ፡ ከተማ ÷ ደስታ ፡ ያለሽ ፡ ከተማ ፡
ሆይ ÷ በአንቺ ፡ ውስጥ ፡ የተገደሉት ፡ በሰይፍ ፡
የተገደሉ ፡ አይደሉም ÷ በሰልፍም ፡ የሞቱ ፡
፫ አይደሉም ። አለቆችሽ ፡ ሁሉ ፡ በአንድነት ፡
ሸሹ ÷ ያለ ፡ ቀስትም ፡ ተማረኩ ፤ ከሩቅ ፡ ሸሽ
ተው ፡ ከአንቺ ፡ ዘንድ ፡ የተገኙት ፡ ሁሉ ፡ በአ
፬ ንድነት ፡ ታሰሩ ። ስለዚህ ፡— ፊታችሁን ፡ ከእኔ ፡
ዘንድ ፡ አርቁ ፤ መራራ ፡ ልቅሶ ፡ አለቅሳለሁ ፤
ስለ ፡ ሕዝቤ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ጥፋት ፡ ታጽናኑኝ ፡
ዘንድ ፡ አትድከሙ ÷ አልሁ ።
፭ ከሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
የድንጋጤና ፡ የመረገጥ ፡ የድብልቅልቅም ፡
ቀን ÷ የቅጥርም ፡ መፍረስ ፡ ወደ ፡ ተራራም ፡
መጮኽ ፡ በራእይ ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ ሆኖአል ።
፮ ኤላምም ፡ ከሰረገለኞችና ፡ ከፈረሰኞች ፡ ጋር ፡
ሆኖ ፡ አፎቱን ፡ ተሸከመ ÷ ቂርም ፡ ጋሻውን ፡
፯ ገለጠ ። መልካሞቹንም ፡ ሸለቆችሽን ፡ ሰረ
ገሎች ፡ ሞሉባቸው ÷ ፈረሰኞችም ፡ መቆሚ
፰ ያቸውን ፡ በበር ፡ ላይ ፡ አደረጉ ። የይሁዳ
ንም ፡ መጋረጃ ፡ ገለጠ ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡
በዱር ፡ ቤት ፡ የነበረውን ፡ የጦር ፡ ዕቃ ፡ ተመለ
፱ ከትህ ÷ የዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ፍራሾች ፡ እንደ ፡
በዙ ፡ አይታችኋል ÷ የታችኛውንም ፡ ኵሬ ፡
፲ ውኃ ፡ አከማችታችኋል ÷ የኢየሩሳሌምን ፡
ቤቶች ፡ ቈጠራችሁ ÷ ቅጥሩንም ፡ ለማጥናት ፡
፲፩ ቤቶችን ፡ አፈረሳችሁ ። በአሮጌው ፡ ኵሬ ፡
ላለው ፡ ውኃ ፡ በሁለቱ ፡ ቅጥር ፡ መካከል ፡ መከ
ማቻ ፡ ሠራችሁ ፤ ይህን ፡ ያደረገውን ፡ ግን ፡
አልተመለከታችሁም ÷ ቀድሞ ፡ የሠራውንም ፡
አላያችሁም ።
፲፪ በዚያም ፡ ቀን ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ወደ ፡ ልቅሶና ፡ ወደ ፡ ዋይታ ፡ ራስን ፡
ወደ ፡ መንጨትና ፡ ማቅንም ፡ ወደ ፡ መልበስ ፡
፲፫ ጠራ ። እነሆም ÷ ሐሤትና ፡ ደስታ ፡ በሬውንና ፡
በጉንም ፡ ማረድ ፡ ሥጋንም ፡ መብላት ፡ የወይን ፡
ጠጅንም ፡ መጠጣት ፡ ሆነዋል ፤ እናንተ ፡—
ነገ ፡ እንሞታለንና ፡ እንብላ ፡ እንጠጣ ፡ ብላች
፲፬ ኋል ። ይህም ፡ ነገር ፡ በሠራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ጆሮ ፡ ተሰማ ፡— እስክትሞቱ ፡
ድረስ ፡ ይህ ፡ በደል ፡ በእውነት ፡ አይሰረይላች
ሁም ፡ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።
የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ፲፭
ይላል ፡— በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ወደ ፡ ተሾመው ፡
ወደዚህ ፡ አዛዥ ፡ ወደ ፡ ሳምናስ ፡ ሂድ ፡ እንዲ
ህም ፡ በለው ፡— መቃብር ፡ በዚህ ፡ ያስወቀርህ ÷ ፲፮
ከፍ ፡ ባለው ፡ ስፍራ ፡ መቃብር ፡ ያሠራህ ÷
በድንጋይም ፡ ውስጥ ፡ ለራስህ ፡ መኖርያ ፡ ያሰ
ነጽህ ፡ በዚህ ፡ ምን ፡ አለህ ? በዚህስ ፡ በአንተ ፡
ዘንድ ፡ ማን ፡ አለ ? እነሆ ÷ እግዚአብሔር ፡ ፲፯
በኃይል ፡ ወርውሮ ፡ ይጥልሃል ÷ አጠንክሮም ፡
ይጨብጥሃል ። ጠቅልሎም ፡ ያንከባልልሃል ፡ ፲፰
ወደ ፡ ሰፊይቱም ፡ ምድር ፡ እንደ ፡ ኳስ ፡ ይጥል
ሃል ፤ አንተ ፡ የጌታህ ፡ ቤት ፡ እፍረት ! በዚያ ፡
ትሞታለህ ፡ በዚያም ፡ የክብርህ ፡ ሰረገላዎች ፡
ይሆናሉ ። ከአዛዥነት ፡ ሥራህ ፡ አሳድድሃለሁ ÷ ፲፱
ከሹመትህም ፡ ትሻራለህ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ባሪ ፳
ያዩን ፡ የኬልቅያስን ፡ ልጅ ፡ ኤልያቄምን ፡ እጠ
ራለሁ ÷ መጐናጸፊያህንም ፡ አለብሰዋለሁ ÷ ፳፩
በመታጠቂያህም ፡ አስታጥቀዋለሁ ÷ ሹመትህ
ንም ፡ በእጁ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጠዋለሁ ፤ በኢ
የሩሳሌምም ፡ ለሚኖሩ ፡ ለይሁዳም ፡ ቤት ፡
አባት ፡ ይሆናል ። የዳዊትንም ፡ ቤት ፡ መክ ፳፪
ፈቻ ፡ በጫንቃው ፡ ላይ ፡ አኖራለሁ ፤ እርሱም ፡
ይከፍታል ፡ የሚዘጋም ፡ የለም ፤ እርሱም ፡ ይዘ
ጋል ፡ የሚከፍትም ፡ የለም ። በታመነም ፡ ስፍራ ፡ ፳፫
እንደ ፡ ችንካር ፡ እተክለዋለሁ ÷ ለአባቱም ፡
ቤት ፡ የክብር ፡ ዙፋን ፡ ይሆናል ። የአባቱንም ፡ ፳፬
ቤት ፡ ክብር ፡ ሁሉ ፡ ልጆቹንም ፡ የልጅ ፡ ልጆ
ቹንም ÷ ከጽዋ ፡ ዕቃ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ማድጋ ፡
ዕቃ ፡ ድረስ ÷ ታናናሹን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ይሰቅ
ሉበታል ። በዚያ ፡ ቀን ÷ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ፳፭
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ÷ በታመነው ፡ ስፍራ ፡ የተ
ተከለው ፡ ችንካር ፡ ይወልቃል ፤ ተሰብሮም ፡
ይወድቃል ÷ በእርሱም ፡ ላይ ፡ የተሰቀለው ፡
ሸክም ፡ ይጠፋል ፤ እግዚአብሔር ፡ ተናግሮአ
ልና ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

ስለ ፡ ጢሮስ ፡ የተነገረ ፡ ሸክም ። ፩
የተርሴስ ፡ መርከቦች ፡ ሆይ ÷ አልቅሱ ፤ ፈር
ሶአልና ፡ ቤት ፡ የለም ÷ መግቢትም ፡ የለም ፤
ከኪቲም ፡ አገር ፡ ጀምሮ ፡ ተገልጦላቸዋል ።
እናንተ ፡ በደሴት ፡ የምትኖሩ ፡ በባሕርም ፡ የሚ ፪
ሻገሩ ፡ የሲዶና ፡ ነጋዴዎች ፡ ንግድ ፡ የሞሉብ
ችሁ ፡ ሆይ ÷ ጸጥ ፡ በሉ ። የሺሖር ፡ ዘርና ፡ ፫
የዓባይ ፡ ወንዝ ፡ መከር ፡ በብዙ ፡ ውኆች ፡ ላይ ፡
ገቢዋ ፡ ነበረ ፤ እርስዋም ፡ የአሕዛብ ፡ መናገጃ ፡
ነበረች ። ሲዶና ፡ ሆይ ÷ ባሕር ÷ የባሕር ፡ ፬
ምሽግ ፡— አላማጥሁም ÷ አልወለድሁም ፤ ጐበዛ
ዝትንም ፡ አላሳደግሁም ÷ ደናግልንም ፡ አላሳደ
ግሁም ፡ ብሎ ፡ ተናግሮአልና ፡ እፈሪ ። ወሬዋ ፡ ፭
ወደ ፡ ግብጽ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ በጢሮስ ፡ ወሬ ፡
ምጥ ፡ ይይዛቸዋል ። ወደ ፡ ተርሴስ ፡ ተሻገሩ ፤ ፮
እናንተ ፡ በደሴት ፡ የምትኖሩ ፡ አልቅሱ ። በቀ ፯

ድሞ ፡ ዘመን ፡ ተመሥርታ ፡ የነበረችው ÷ በዚ
ያም ፡ እንደ ፡ እንግዳ ፡ ሆና ፡ ትኖር ፡ ዘንድ ፡
እግሮችዋ ፡ ወደ ፡ ሩቅ ፡ ያፈለሱአት ፡ የደስታ
፰ ችሁ ፡ ከተማ ፡ ይህች ፡ ናትን ? አክሊል ፡ በስ
ጫነች ፡ ከተማ ፡ በጢሮስ ፡ ላይ ፡ ይህን ፡ የወሰነ ፡
ማን ፡ ነው ? ነጋዴዎችዋ ፡ አለቆች ፡ ናቸው ÷
በእርስዋም ፡ የሚሸጡና ፡ የሚለውጡ ፡ የም
፱ ድር ፡ ክቡራን ፡ ናቸው ። የክብርን ፡ ሁሉ ፡ ትዕ
ቢት ፡ ይሽር ፡ ዘንድ ፡ የምድርንም ፡ ክቡራን ፡
ሁሉ ፡ ያስንቅ ፡ ዘንድ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግ
፲ ዚአብሔር ፡ ወስኖታል ። የተርሴስ ፡ ልጅ ፡
ሆይ ÷ የሚከለክልሽ ፡ የለምና ፡ እንደ ፡ ዓባይ ፡
፲፩ ወንዝ ፡ በአገርሽ ፡ ላይ ፡ ጐርፈሽ ፡ እለፊ ። በባ
ሕር ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ ዘረጋ ፤ መንግሥታትንም ፡
አናወጠ ፤ ምሽጎችዋንም ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ እግ
፲፪ ዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ከነዓን ፡ አገር ፡ አዘዘ ። እር
ሱም ፡— አንቺ ፡ የተበደልሽ ፡ የሲዶና ፡ ድን
ግል ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ደስ ፡
አይበልሽ ፤ ተነሥተሽ ፡ ወደ ፡ ኪቲም ፡ ተሻገሪ ÷
፲፫ በዚያም ፡ ደግሞ ፡ አታርፊም ፡ አለ ። እነሆ ÷
የከለዳውያን ፡ አገር ፤ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ሆኖ ፡ አይ
ገኝም ፤ አሦራውያን ፡ ለምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊት ፡
ሰጥተውታል ፤ ግንቦቻቸውን ፡ ሠሩ ÷ አዳራሾ
ችዋንም ፡ አፈረሱ ÷ በድማም ፡ አደረጓት ።
፲፬ እናንተ ፡ የተርሴስ ፡ መርከቦች ፡ ሆይ ÷ ምሽጋ
ችሁ ፡ ፈርሶአልና ፡ ዋይ ፡ በሉ ።

፲፭ በዚያም ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ፤ ጢሮስ ፡
እንደ ፡ አንድ ፡ ንጉሥ ፡ ዘመን ፡ ሰባ ፡ ዓመት ፡
ያህል ፡ የተረሳች ፡ ትሆናለች ፤ ከሰባ ፡ ዓመት ፡
በኋላ ፡ ግን ፡ ለጢሮስ ፡ በጋለሞታ ፡ ዘፈን ፡ እን
፲፮ ደሚሆን ፡ እንዲሁ ፡ ይሆናል ። አንቺ ፡ የተረ
ሳሽ ፡ ጋለሞታ ፡ ሆይ ÷ መሰንቆ ፡ ያዝ ፡ በከተማ ፡
ላይም ፡ ዙሪ ፤ መታሰቢያም ፡ ይሆንልሽ ፡ ዘንድ ፡
፲፯ ዜማን ፡ አሳምሪ ፡ ዘፈንሽንም ፡ አብዢ ። ከሰባ ፡
ዓመትም ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጢሮስን ፡
ይጐበኛታል ÷ ወደ ፡ ዋጋዋም ፡ ትመለሳለች ÷
ደግሞም ፡ በምድር ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ ከሆኑ ፡ ከዓለም ፡
መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ትገለሙታለች ።
፲፰ ንግድዋና ፡ ዋጋዋ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ ፡
ይሆናል ፤ ንግድዋም ፡ በልተው ፡ ይጠግቡ ፡
ዘንድ ፡ ማለፊያም ፡ ልብስ ፡ ይለብሱ ፡ ዘንድ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለሚኖሩ ፡ ይሆናል ፡
እንጂ ፡ በዕቃ ፡ ቤትና ፡ በግምጃ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡
አይከተትም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ እነሆ ÷ እግዚአብሔር ፡ ምድርን ፡ ባዶ ፡ ያደር
ጋታል ÷ በድማም ፡ ያደርጋታል ÷ ይገለብጣ
ትማል ÷ በእርስዋም ፡ የተቀመጡትን ፡ ይበት
፪ ናል ። እንደ ፡ ሕዝቡም ፡ እንዲሁ ፡ ካህኑ ÷ እንደ ፡
ባሪያውም ፡ እንዲሁ ፡ ጌታው ÷ እንደ ፡ ባሪያይ
ቱም ፡ እንዲሁ ፡ እመቤትዋ ÷ እንደሚገዛም ፡
እንዲሁ ፡ የሚሸጠው ÷ እንደ ፡ አበዳሪውም ፡
እንዲሁ ፡ ተበዳሪው ÷ እንደ ፡ ዕዳ ፡ አስከፋዩም ፡
እንዲሁ ፡ ዕዳ ፡ ከፋዩ ፡ ይሆናል ። ፫ ምድር ፡ መፈ
ታትን ፡ ትፈታለች ÷ ፈጽማም ፡ ትበላሻለች ፤
እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ተናግሮአልና ።
፬ ምድርም ፡ አለቀሰች ፡ ረገፈችም ፤ ዓለም ፡ ደከ
መች ፡ ረገፈችም ፤ የምድርም ፡ ሕዝብ ፡ ታላላ
ቆች ፡ ደከሙ ። ፭ ምድርም ፡ ከሚቀመጡባት ፡
በታች ፡ ረከሰች ÷ ሕጉን ፡ ተላልፈዋልና ÷
ሥርዓቱንም ፡ ለውጠዋልና ÷ የዘላለሙንም ፡
ቃል ፡ ኪዳን ፡ አፍርሰዋልና ። ፮ ስለዚህ ፡ መር
ገም ፡ ምድርን ፡ ትበላለች ፡ በእርስዋም ፡ የተቀ
መጡ ፡ ይቀጣሉ ፤ ስለዚህ ፡ የምድር ፡ ሰዎች ፡
ይቃጠላሉ ፡ ጥቂት ፡ ሰዎችም ፡ ይቀራሉ ። ፯ የወ
ይን ፡ ጠጅ ፡ አለቀሰች ÷ የወይን ፡ ግንድ ፡ ደከ
መች ÷ ልባቸው ፡ ደስ ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ ተከዙ ።
፰ የከበሮው ፡ ሐሤት ፡ ቀርቶአል ÷ የደስተኞች ፡
ድምፅ ፡ ዝም ፡ ብሎአል ÷ የመሰንቆ ፡ ደስታ ፡
ቀርቶአል ። ፱ እየዘፈኑም ፡ የወይን ፡ ጠጅን ፡ አይጠ
ጡትም ÷ የሚያሰክርም ፡ መጠጥ ፡ ለሚጠጡት ፡
መራራ ፡ ይሆናል ። ፲ በድማ ፡ የሆነችው ፡ ከተማ ፡
ፈረሰች ፤ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ማንም ፡ እንዳይገባበት ፡
ተዘጋ ። ፲፩ ስለ ፡ ወይኑም ፡ ጠጅ ፡ በአደባባይ ፡
ጩኸት ፡ ይሆናል ፤ ደስታ ፡ ሁሉ ፡ ጨልሞአል ÷
የምድርም ፡ ሐሤት ፡ ፈልሶአል ። ፲፪ ከተማይቱም ፡
በድማ ፡ ሆናለች ÷ በርዋም ፡ በጥፋት ፡ ተመት
ቶአል ። ፲፫ የወይራን ፡ ዛፍ ፡ እንደ ፡ መምታት ÷
ከወይንም ፡ መከር ፡ በኋላ ፡ ቃርሚያውን ፡ እንደ ፡
መልቀም ÷ እንዲሁ ፡ በምድር ፡ መካከል ፡ በአ
ሕዛብም ፡ መካከል ፡ ይሆናል ።

፲፬ እነዚህ ፡ ድምፃቸውን ፡ ያነሣሉ ÷ እልልም ፡
ይላሉ ÷ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ክብርም ፡ ከባ
ሕር ፡ ይጮኻሉ ። ፲፭ ስለዚህ ፡ እግዚአብሔርን ፡
በምሥራቅ ÷ የእስራኤልንም ፡ አምላክ ፡ የእግዚ
አብሔርንም ፡ ስም ፡ በባሕር ፡ ደሴቶች ፡ አክብሩ ።

፲፮ ለጻድቅ ፡ ክብር ፡ ይሁን ፡ የሚለውን ፡ ዝማሬ ፡
ከምድር ፡ ዳርቻ ፡ ሰምተናል ። እኔ ፡ ግን ፡—
ከሳሁ ÷ ከሳሁ ÷ ወዮልኝ ! ወንጀለኞች ፡ ወን
ጀለዋል ፤ ወንጀለኞች ፡ እጅግ ፡ ወንጀለዋል ፡
አልሁ ። ፲፯ በምድር ፡ ላይ ፡ የምትኖር ፡ ሆይ ÷
ፍርሃትና ፡ ገደል ፡ ወጥመድም ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡
አሉ ። ፲፰ የሰማይ ፡ መስኮቶች ፡ ተከፍተዋልና ÷
የምድርም ፡ መሠረት ፡ ተናውጣለችና ፡ ከፍር
ሃት ፡ ድምፅ ፡ የሸሸ ፡ በገደል ፡ ይወድቃል ÷
ከገደልም ፡ የወጣ ፡ በወጥመድ ፡ ይያዛል ።
፲፱ ምድር ፡ ተሰባበረች ÷ ምድር ፡ ፈጽማ ፡ ደቀ
ቀች ÷ ምድር ፡ ተነዋወጠች ። ፳ ምድር ፡ እንደ ፡
ሰካር ፡ ሰው ፡ ትንገደገዳለች ÷ እንደ ፡ ዳስም ፡
ትወዛወዛለች ፤ መተላለፍዋ ፡ ይከብድባታል ÷
ትወድቅማለች ፡ ደግማም ፡ አትነሣም ።

፳፩ በዚያም ፡ ቀን ፡ እንደዚህ ፡ ይሆናል ፤ እግዚአ
ብሔር ፡ በከፍታ ፡ ያለውን ፡ ሠራዊት ፡ በከፍታ ፡
ላይ ÷ በምድርም ፡ ያሉትን ፡ ነገሥታት ፡ በም
ድር ፡ ላይ ፡ ይቀጣቸዋል ። ፳፪ ግዞተኞች ፡ በጕድ
ጓድ ፡ እንደሚከማቹ ፡ በአንድነት ፡ ይከማቻሉ ÷
በግዞት ፡ ቤትም ፡ ውስጥ ፡ ተዘግተው ፡ ይኖ

ራሉ ÷ ከብዙ ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ይጐበኛሉ ።
፳፫ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በጽዮን ፡ ተራራና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ ይነግሣልና ÷ በሽማግሌዎቹም ፡ ፊት ፡ ክብር ፡ ይሆናልና ፡ ጨረቃ ፡ ይታወከል ፡ ፀሐይም ፡ ያፍራል ።

## ምዕራፍ ፳፭ ።

፩ አቤቱ ÷ አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነህ ፤ ድንቅን ፡ ነገር ፡ የዱሮ ፡ ምክርን ፡ በታማኝነትና ፡ በእውነት ፡ አድርገሃልና ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርግሃለሁ ፡ ስምህ
፪ ንም ፡ አመሰግናለሁ ። ከተማይቱን ፡ የድንጋይ ፡ ክምር ÷ የተመሸገችውን ፡ ከተማ ፡ ውድማ ፡ እንድትሆን ÷ የኅጥአንንም ፡ አዳራሽ ፡ ከተማ ፡ እንዳትሆን ፡ አድርገሃል ፤ ከቶ ፡ አትሠራም ።
፫ ስለዚህ ፡ ኃያላኑ ፡ ወገኖች ፡ ያከብሩሃል ÷ የጨ
፬ ካኞች ፡ አሕዛብ ፡ ከተማም ፡ ትፈራሃለች ። የጨካኞችም ፡ ቍጣ ፡ እስትንፋስ ፡ ቅጥርን ፡ እንደሚመታ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ÷ ለድሀው ፡ መጠጊያ ÷ ለችግረኛው ፡ በጭንቁ ፡ ጊዜ ፡ መጠጊያ ÷ ከውሽንፍር ፡ መሸሸጊያ ፡ ከሙቀ
፭ ትም ፡ ጥላ ፡ ሆንሃል ። እንደ ፡ ሙቀት ፡ በደረቅ ፡ ስፍራ ፡ የኅጥአንን ፡ ጩኸት ፡ ዝም ፡ ታሰኛለህ ፤ ሙቀትም ፡ በደመና ፡ ጥላ ፡ እንዲበርድ ፡ እንዲሁ ፡ የጨካኞች ፡ ዝማሬ ፡ ይዋረዳል ።
፮ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ለሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ በዚህ ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ የሰባ ፡ ግብዣ ÷ ያረጀ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ÷ ቅልጥም ፡ የሞላባቸው ፡ የሰቡ ፡ ነገሮች ÷ የጥሩና ፡ ያረጀ ፡
፯ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ግብዣ ፡ ያደርጋል ። በዚህም ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ በወገኖች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የተጣለውን ፡ መጋረጃ ÷ በአሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የተዘረጋ
፰ ውን ፡ መሸፈኛ ፡ ያጠፋል ። ሞትን ፡ ለዘላለም ፡ ይውጣል ÷ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ከፊት ፡ ሁሉ ፡ እንባን ፡ ያብሳል ÷ የሕዝቡንም ፡ ስድብ ፡ ከምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያስወግዳል ፤ እግዚአብሔር ፡ ተናግሮአልና ።
፱ በዚያም ፡ ቀን ፡— እነሆ ÷ አምላካችን ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ተስፋ ፡ አድርገነዋል ÷ ያድነንማል ፤ እግዚአብሔር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ጠብቀነዋል ፤ በማዳኑ ፡ ደስ ፡ ይለናል ፡ ሐሤትም ፡ እናደርጋለን ፡ ይባ
፲ ላል ። የእግዚአብሔርም ፡ እጅ ፡ በዚህ ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ታርፋለች ÷ ጭድም ፡ በጭቃ ፡ ውስጥ ፡ እንደሚረገጥ ፡ እንዲሁ ፡ ሞዓብ ፡ በስፍራው ፡
፲፩ ይረገጣል ። ዋናተኛም ፡ ሲዋኝ ፡ እጁን ፡ እንደሚዘረጋ ÷ እንዲሁ ፡ በመካከሉ ፡ እጁን ፡ ይዘረጋል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ትዕቢቱን ፡
፲፪ ከእጁ ፡ ተንኰል ፡ ጋር ፡ ያዋርዳል ። የተመሸገውንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያለውንም ፡ ቅጥርህን ፡ ዝቅ ፡ ያደርገዋል ÷ ያዋርደውማል ÷ ወደ ፡ መሬትም ፡ እስከ ፡ አፈር ፡ ድረስ ፡ ይጥለዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩ በዚያም ፡ ቀን ፡ ይህ ፡ ቅኔ ፡ በይሁዳ ፡ ምድር ፡ ይዘመራል ፡— የጸናች ፡ ከተማ ፡ አለችን ፤ ለቅጥርና ፡ ለምሽግ ፡ መድኃኒትን ፡ ያኖርበታል ።
፪ እውነትን ፡ የሚጠብቅ ፡ ጻድቅ ፡ ሕዝብ ፡ ይገባ ፡
፫ ዘንድ ፡ በሮችን ፡ ክፈቱ ። በአንተ ፡ ላይ ፡ ታምናለችና ፡ በአንተ ፡ ለምትደገፍ ፡ ነፍስ ፡ ፈጽመህ ፡
፬ በሰላም ፡ ትጠብቃታለህ ። ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ የዘላለም ፡ አምባ ፡ ነውና ፡ ለዘላለም ፡ በእግዚ
፭ አብሔር ፡ ታመኑ ። በከፍታ ፡ የሚኖሩትን ፡ ሰዎች ፡ ዝቅ ፡ ያደርጋል ፤ ከፍ ፡ ያለችውን ፡ ከተማ ፡ ያዋርዳል ÷ እስከ ፡ መሬትም ፡ ድረስ ፡ ያወርዳታል ÷ እስከ ፡ አፈርም ፡ ድረስ ፡ ይጥላ
፮ ታል ። እግር ÷ የድሀ ፡ እግርም ፡ የችግረኛም ፡ እረጋገጥ ÷ ትረግጣታለች ።
፯ የጻድቃን ፡ መንገድ ፡ ቅን ፡ ናት ፤ አንተ ፡ ቅን ፡ የሆንህ ፡ የጻድቃንን ፡ መንገድ ፡ ታቃናለህ ።
፰ አቤቱ ÷ በፍርድህ ፡ መንገድ ፡ ተስፋ ፡ አድርገ ንሃል ÷ ስምህም ፡ መታሰቢያህም ፡ የነፍሳችን ፡
፱ ምኞት ፡ ነው ። ፍርድህን ፡ በምድር ፡ ባደረግህ ፡ ጊዜ ፡ በዓለም ፡ የሚኖሩ ፡ ጽድቅን ፡ ይማራሉና ፡ ነፍሴ ፡ በሌሊት ፡ ትናፍቅሃለች ÷ መንፈሴም ፡
፲ በውስጤ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ትገሠግሣለች ። ለኃጢአተኛ ፡ ሞገስ ፡ ቢደረግለት ፡ ጽድቅን ፡ አይማርም ፤ በቅኖች ፡ ምድር ፡ ክፉን ፡ ነገር ፡ ያደርጋል ÷ የእግዚአብሔርንም ፡ ግርማ ፡ አያይም ።
፲፩ አቤቱ ÷ እጅህ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለች ፡ አላዩምም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በሕዝብህ ፡ ላይ ፡ ያለህን ፡ ቅንዓት ፡ አይተው ፡ ያፍራሉ ፤ እሳትም ፡ ጠላቶ
፲፪ ችህን ፡ ትበላለች ። አቤቱ ÷ ሥራችንን ፡ ሁሉ ፡
፲፫ ሠርተህልናልና ፡ ሰላምን ፡ ትሰጠናለህ ። አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ሆይ ÷ ከአንተ ፡ በቀር ፡ ሌሎች ፡ ጌቶች ፡ ገዝተውናል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በአንተ ፡
፲፬ ብቻ ፡ ስምህን ፡ እናስባለን ። እነርሱ ፡ ሞተዋል ÷ በሕይወት ፡ አይኖሩም ፤ ጠፍተዋል ÷ አይነሡም ፤ ስለዚህ ፡ አንተ ፡ ጐብኝተሃቸዋል ፡ አጥፍተሃቸውማል ÷ መታሰቢያቸውንም ፡ ሁሉ ፡
፲፭ ምንምን ፡ አድርገሃል ። ሕዝብን ፡ አበዛህ ÷ አቤቱ ÷ ሕዝብን ፡ አበዛህ ፤ አንተም ፡ ተከበርህ ÷ የአገሪቱንም ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ አሰፋህ ።
፲፮ አቤቱ ÷ በመከራ ፡ ጊዜ ፡ ፈለጉህ ÷ በገሠጽሃቸውም ፡ ጊዜ ፡ ልመናቸውን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ አፈ
፲፯ ሰሱ ። የፀነሰች ፡ ሴት ፡ ለመውለድ ፡ ስትቀርብ ፡ እንደምትጨነቅና ፡ በምጥ ፡ እንደምትጮኽ ÷
፲፰ አቤቱ ÷ እንዲሁ ፡ በፊትህ ፡ ሆነናል ። እኛ ፡ ፀንሰናል ፡ ምጥም ፡ ይዞናል ÷ ነፋስንም ፡ እንደምንወልድ ፡ ሆነናል ፤ በምድርም ፡ ደኅንነት ፡ አላደረግነም ፤ በዓለምም ፡ የሚኖሩ ፡ ይወድቃሉ ።
፲፱ ሙታንህ ፡ ሕያዋን ፡ ይሆናሉ ÷ ሬሳዎችም ፡ ይነሣሉ ። በምድር ፡ የምትኖሩ ፡ ሆይ ÷ ጠልህ ፡ የብርሃን ፡ ጠል ፡ ነውና ÷ ምድርም ፡ ሙታንን ፡ ታወጣለችና ፡ ንቁ ፡ ዘምሩም ።
፳ ሕዝቤ ፡ ሆይ ÷ ና ፡ ወደ ፡ ቤትህም ፡ ግባ ÷ ደጅህን ፡ በኋላህ ፡ ዝጋ ፤ ቍጣ ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፡
፳፩ ጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ተሸሸግ ። በምድር ፡ በሚኖሩት ፡ ላይ ፡ በበደላቸው ፡ ምክንያት ፡ ቍጣውን ፡ ያመጣባቸው ፡ ዘንድ ÷ እነሆ ÷ እግዚአብሔር ፡ ከስ

ፍራው ፡ ይወጣል ፤ ምድርም ፡ ደምዋን ፡ ትገልጣለች ፥ ሙታኖችዋንም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አትከድንም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

፩ በዚያም ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈጣኑን ፡ እባብ ፡ ሌዋታንን ፡ ጠማማውንም ፡ እባብ ፡ ሌዋታንን ፡ በጠንካራ ፡ በታላቅም ፡ በብርቱም ፡ ሰይፍ ፡ ይቀጣል ፥ በባሕርም ፡ ውስጥ ፡ ያለውን ፡ ዘንዶ ፡ ይገድላል ።

፪ በዚያም ፡ ቀን ፡ ለተወደደው ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ ፫ ተቀኙለት ። እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጠባቂው ፡ ነኝ ፤ ሁልጊዜ ፡ አጠጣዋለሁ ፤ ማንም ፡ እንዳይጐዳው ፡ በሌሊትና ፡ በቀን ፡ እጠብቀዋለሁ ። ፬ አልቈጣም ፤ እሾህና ፡ ኵርንችት ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ምነው ፡ በሰልፍ ፡ በነበሩ ! በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ተራምጄ ፡ በአንድነት ፡ ባቃጠልኋቸው ፡ ነበር ። ፭ ወይም ፡ ጕልበቴን ፡ ይያዝ ፥ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ሰላም ፡ ፮ ያድርግ ፤ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ሰላም ፡ ያድርግ ። በሚመጣው ፡ ዘመን ፡ ያዕቆብ ፡ ሥር ፡ ይሰድዳል ፥ እስራኤልም ፡ ያብባል ፡ ይጨበጭብማል ፤ በፍሬያቸውም ፡ የዓለሙን ፡ ፊት ፡ ይሞላሉ ።

፯ በውኑ ፡ የመቱትን ፡ እንደ ፡ መታ ፡ እንዲሁ ፡ እርሱን ፡ መታውን ? ወይስ ፡ እነርሱ ፡ እንደ ፡ ተገደሉበት ፡ መገደል ፡ እርሱ ፡ ተገድሎአልን ? ፰ ነዳቸው ፡ ሰደዳቸው ፡ ቀሠፋቸው ፤ የምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ እንደሚነፍስበት ፡ ቀን ፡ በጠንካራ ፡ ፱ ዐውሎ ፡ አስወገዳቸው ። ስለዚህም ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶችና ፡ የፀሐይ ፡ ምስሎች ፡ ዳግመኛ ፡ እንዳይነሡ ፡ የመሠዊያውን ፡ ድንጋይ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ደቀቀ ፡ እንደ ፡ ኖራ ፡ ድንጋይ ፡ ባደረገ ፡ ጊዜ ፥ እንዲሁ ፡ የያዕቆብ ፡ በደል ፡ ይሰረያል ፥ ይህም ፡ ኃጢአትን ፡ የማስወገድ ፡ ፍሬ ፡ ሁሉ ፡ ፲ ነው ። የተመሸገችው ፡ ከተማ ፡ ብቻዋን ፡ ሆነች ፤ እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሆና ፡ የተፈታችና ፡ የተተወች ፡ መኖሪያ ፡ ናት ፤ በዚያም ፡ ጥጃ ፡ ይሰማራል ፡ በዚያም ፡ ይተኛል ፡ ቅርንጫፍዋንም ፡ ፲፩ ይበላል ። ጫሮችዋ ፡ በደረቁ ፡ ጊዜ ፡ ይሰበራሉ ፥ ሴቶችም ፡ መጥተው ፡ ያቃጥሉአቸዋል ፤ የማያስተውል ፡ ሕዝብ ፡ ነውና ፡ ስለዚህ ፡ ፈጣሪው ፡ አይራራለትም ፡ ሠሪውም ፡ ምሕረት ፡ አያደርግለትም ።

፲፪ በዚያም ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ፤ እግዚአብሔር ፡ ከወንዝ ፡ ፈሳሽ ፡ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ግብጽ ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ፡ እህሉን ፡ ይወቃል ፥ እናንተም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ አንድ ፡ በአንድ ፡ ትሰበሰባላችሁ ።

፲፫ በዚያም ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ፤ ታላቅ ፡ መለከት ፡ ይነፋል ፥ በአሦርም ፡ የጠፉ ፥ በግብጽ ፡ ምድርም ፡ የተሰደዱ ፡ ይመጣሉ ፥ በተቀደሰውም ፡ ተራራ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይሰግዳሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

፩ ለኤፍሬም ፡ ሰካሮች ፡ ትዕቢት ፡ አክሊል ፥ በወይን ፡ ጠጅ ፡ ለተሸነፉ ፡ በወፍራም ፡ ሸለቆአቸው ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ላለችም ፡ ለረገፈች ፡ ለክብሩ ፡ ጌጥ ፡ አበባ ፡ ወዮ ! ፪ እነሆ ፥ በጌታ ፡ ዘንድ ፡ ኃያል ፡ ብርቱ ፡ የሆነ ፡ አለ ። እንደ ፡ በረዶ ፡ ወጨፎ ፥ እንደሚያጠፋም ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፥ እንደሚያጥለቀልቅም ፡ እንደ ፡ ታላቅ ፡ ውኃ ፡ ፈሳሽ ፡ በጠንከረ ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ይጥላል ። ፫ የኤፍሬም ፡ ሰካሮች ፡ ትዕቢት ፡ አክሊል ፡ በእግር ፡ ይረገጣል ፤ ፬ በወፍራሙ ፡ ሸለቆ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ያለች ፡ የረገፈች ፡ የክብሩ ፡ ጌጥ ፡ አበባ ፡ ከመከር ፡ በፊት ፡ አስቀድማ ፡ እንደምትበስል ፡ በለስ ፡ ትሆናለች ፤ ሰው ፡ ባያት ፡ ጊዜ ፡ በእጁ ፡ እንዳለች ፡ ይበላታል ። ፭ በዚያ ፡ ቀን ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለቀሩት ፡ ሕዝቡ ፡ የክብር ፡ ዘውድና ፡ የጌጥ ፡ አክሊል ፡ ይሆናል ፤ ፮ በፍርድ ፡ ወንበር ፡ ላይ ፡ ለሚቀመጥም ፡ የፍርድ ፡ መንፈስ ፥ ሰልፉን ፡ ወደ ፡ በር ፡ ለሚመልሱም ፡ ኃይል ፡ ይሆናል ።

፯ እነዚህም ፡ ደግሞ ፡ ከወይን ፡ ጠጅ ፡ የተነሣ ፡ ይስታሉ ፥ ከሚያሰክርም ፡ መጠጥ ፡ የተነሣ ፡ ይፋንናሉ ፤ ካህኑና ፡ ነቢዩ ፡ ከሚያሰክር ፡ መጠጥ ፡ የተነሣ ፡ ይስታሉ ፥ በወይን ፡ ጠጅም ፡ ይዋጣሉ ፥ ከሚያሰክርም ፡ መጠጥ ፡ የተነሣ ፡ ይፋንናሉ ፤ በራእይ ፡ ይስታሉ ፥ በፍርድም ፡ ይሰናከላሉ ። ፰ ማዕዱ ፡ ሁሉ ፡ ትፋትንና ፡ ርኵሰትን ፡ ተሞልቶአታል ፤ ንጹሕ ፡ ስፍራ ፡ እንኳ ፡ የለም ።

፱ እውቀትን ፡ ለማን ፡ ያስተምረዋል ? ወይስ ፡ ወሬ ፡ ማስተዋልን ፡ ለማን ፡ ይሰጣል ? ወተትን ፡ ለተዉ ፡ ወይስ ፡ ጡትን ፡ ለጣሉ ፡ ነውን ? ፲ ትእዛዝ ፡ በትእዛዝ ፥ ትእዛዝ ፡ በትእዛዝ ፥ ሥርዓት ፡ በሥርዓት ፥ ሥርዓት ፡ በሥርዓት ፥ ጥቂት ፡ በዚህ ፡ ጥቂት ፡ በዚያ ፡ ነው ። ፲፩ በባዕድ ፡ አፍ ፡ በልዩም ፡ ልሳን ፡ ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ይናገራል ፤ ፲፪ እርሱም ፦ ዕረፍት ፡ ይህች ፡ ናት ፥ የደከመውን ፡ አሳርፉ ፤ ይህችም ፡ ማረፊያ ፡ ናት ፡ አላቸው ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ መስማትን ፡ እንቢ ፡ አሉ ። ፲፫ ስለዚህ ፡ ሄደው ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ እንዲወድቁ ፡ እንዲሰበሩም ፡ ተጠምደውም ፡ እንዲያዙ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ትእዛዝ ፡ በትእዛዝ ፥ ትእዛዝ ፡ በትእዛዝ ፥ ሥርዓት ፡ በሥርዓት ፥ ሥርዓት ፡ በሥርዓት ፥ ጥቂት ፡ በዚህ ፡ ጥቂት ፡ በዚያ ፡ ይሆንላቸዋል ።

፲፬ ስለዚህ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያለውን ፡ ሕዝብ ፡ የምትገዙ ፡ ፌዘኞች ፡ ሆይ ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስሙ ። ፲፭ እናንተም ፦ ከሞት ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አድርገናል ፥ ከሲኦልም ፡ ጋር ፡ ተማምለናል ፤ ሐሰትን ፡ መሸሸጊያችን ፡ አድርገናልና ፥ በሐሰትም ፡ ተሰውረናልና ፡ የሚትረፈረፍ ፡ መቅሠ

ፍት፡በለፈ፡ጊዜ፡አይደርስብንም፡ ስላላችሁ÷
፲፮ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እነሆ ÷ በጽዮን ፡ ድንጋይን ፡ ለመ
ሠረት፡ አስቀምጣለሁ ፤ የተፈተነውን ÷ የከበረ
ውን÷መሠረቱ፡የጸናውን፡የማዕዘን፡ድንጋይ፤
፲፯ የሚያምንም ፡ አያፍርም ። ለገመድ ፡ ፍርድን ፡
ለቱንቢም ፡ ጽድቅን ፡ አደርጋለሁ ፤ በረዶውም ፡
የሐሰትን ፡ መሸሸጊያ ፡ ይጠርጋል ÷ ውኆችም ፡
፲፰ መሰወሪያውን ፡ ያሰጥማሉ ። ከሞትም ፡ ጋር ፡
ያደረጋችሁት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ይፈርሳል ÷ ከሲ
ኦልም ፡ ጋር ፡ የተማማላችሁት ፡ መሐላ ፡ አይ
ጸናም ፤ የሚትረፈረፍ ፡ መቅሠፍት ፡ በለፈ ፡
፲፱ ጊዜ ፡ ትረገጡበታላችሁ ። በለፈም ፡ ጊዜ ፡ ይወ
ስዳችኋል ፤ ማለዳ ፡ ማለዳ ፡ ቀንና ፡ ሌሊት ፡ ያል
ፋል ፤ ወሬውንም ፡ ማስተዋል ፡ ድንጋጤ ፡ ይሆ
፳ ናል ። ሰው ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ተዘርግቶ ፡ ቢተኛ ፡
አልጋው ፡ አጭር ፡ ነው ፤ ሰውም ፡ ሰውነቱን ፡
መሸፈን ፡ ቢወድድ ፡ መጐናጸፊያ ፡ ጠባብ ፡
፳፩ ነው ። እግዚአብሔርም ፡ ሥራውን ፡ ማለት ፡
እንግዳ ፡ ሥራውን ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ÷ አድራጎ
ቱንም ፡ ማለት ፡ ያልታወቀውን ፡ አድራጎቱን ፡
ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ በፐራሲም ፡ ተራራ ፡ እንደ ፡
ነበረ ፡ ይነሣል ÷ በገባዖንም ፡ ሸለቆ ፡ እንደ ፡
፳፪ ነበረ፡ ይቈጣል ። አሁንም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡
የሚጸናውን ፡ የጥፋት ፡ ትእዛዝ ፡ ከሠራዊት ፡
ጌታ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ሰምቻለሁና ፡
እስራት ፡ እንዳይጸናባችሁ ፡ አታፌዙ ።
፳፫ አድምጡ፡ድምፄንም፡ስሙ ፤ ልብ፡አድርጉ፡
፳፬ ንግግሬንም፡ስሙ ። በውኑ፡ገበሬ፡ሊዘራ፡ሁል
ጊዜ ፡ ያርሳልን ? ወይስ ፡ ሁልጊዜ ፡ እርሻውን ፡
፳፭ ይገለግላልን ? ጓሉንስ ፡ ይከስክሳልን ? እር
ሻውን ፡ ባስተካከለ ፡ ጊዜ ፡ ጥቍሩን ፡ አዝ
ሙድ ÷ ከሙኑንም ÷ ስንዴውንም ፡ በተርታ ÷
ገብሱንም ፡ በስፍራው ÷ አጃንም ፡ በደረጃው ፡
፳፮ የሚዘራ ፡ አይደለምን ? ይህንም ፡ ብልሃት ፡
አምላኩ ፡ ያስታውቀዋል ፡ ያስተምረውማል ።
፳፯ ጥቍሩ ፡ አዝሙድ ፡ በተሳለች ፡ ማሄጃ ፡ አያኼ
ድም ÷ የሰረገላም ፡ መንኰራኵር ፡ በከሙን ፡
ላይ ፡ አይዞርም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ጥቍሩ ፡ አዝ
ሙድ ፡ በሽመል ፡ ከሙኑም ፡ በበትር ፡ ይወ
፳፰ ቃል ። የእንጀራ ፡ እህል ፡ ይደቀቃልን ? ለዘ
ላለም ፡ አያኼደውም ፤ የሰረገላውን ፡ መንኰራ
ኵርና ፡ ፈረሶቹን ፡ ምንም ፡ ቢያስኬድበት ፡
፳፱ አያደቅቀውም ። ይህም ፡ ደግሞ ፡ ድንቅ ፡
ምክር ፡ ከሚመክር ፡ በግብሩም ፡ ማለፊያ ፡ ከሆ
ነው ፡ ከሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ወጥቶአል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

፩ ዳዊት ፡ ለሰፈረበት ፡ ከተማ ፡ ለአርኤል ፡
ወዮላት ! ዓመት ፡ በዓመት ፡ ላይ ፡ ጨምሩ ÷
፪ በዓላትም ፡ ይመለሱ ። አርኤልንም ፡ አስጨን
ቃለሁ ÷ ልቅሶና ፡ ዋይታም ፡ ይሆንባታል ፤
፫ እንደ ፡ አርኤልም ፡ ትሆንልኛለች ። በዙሪያ
ሽም ፡ እሰፍራለሁ ÷ በቅጥርም ፡ ከብቤ ፡ አስጨ
ንቅሻለሁ ÷ አምበም ፡ በላይሽ ፡ አቆማለሁ ።
፬ ትዋረጂማለሽ ÷ በመሬትም ፡ ላይ ፡ ሆነሽ ፡ ትና
ገሪያለሽ ÷ ቃልሽም ፡ ዝቅ ፡ ብሎ ፡ ከአፈር ፡
ይወጣል ፤ ድምፅሽም ፡ ከመሬት ፡ እንደሚወጣ ፡
እንደ ፡ መናፍስት ፡ ጠሪ ፡ ድምፅ ፡ ይሆናል ÷
ቃልሽም ፡ ከአፈር ፡ ወጥቶ ፡ ይጮኻል ።
፭ ነገር ፡ ግን ፡ የጠላቶችሽ ፡ ብዛት ፡ እንደ ፡
ደቀቀ ፡ ትቢያ ÷ የጨካኞችም ፡ ብዛት ፡ እንደ
፮ ሚያልፍ ፡ ገለባ ፡ ይሆናል ። ድንገትም ፡ ፈጥኖ ፡
የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በነጐድጓድ ÷
በምድርም ፡ መናወጥ ÷ በታላቅም ፡ ድምፅ ÷
በዐውሎ ፡ ነፋስም ÷ በወጨፎም ÷ በምትበ
፯ ላም ፡ በእሳት ፡ ነበልባል ፡ ይጐበኛታል ። በአ
ርኤልም ፡ ላይ ፡ የሚዋጉ ÷ እርስዋንና ፡ ምሽ
ግዋንም ፡ የሚወጉ ፡ የሚያስጨንቋትም ÷ የአ
ሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ብዛት ፡ እንደ ፡ ሕልምና ፡ እንደ ፡
፰ ሌሊት ፡ ራእይ ፡ ይሆናል ። ተርቦም ፡ እንደሚ
ያልም ፡ ሰው ፡ ይሆናል ፤ በሕልሙም ÷ እነሆ ÷
ይበላል ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ይነቃል ፡ ሰውነቱም ፡
ባዶ ፡ ነው ፤ ተጠምቶም ፡ እንደሚያልም ፡ ሰው ፡
ይሆናል ፤ በሕልሙም ÷ እነሆ ÷ ይጠጣል ÷ ነገር ፡
ግን ፡ ይነቃል ÷ እነሆም ÷ ይዝላል ፡ ሰውነቱም ፡
አምሮት ፡ አለው ፤ እንዲሁ ፡ የጽዮንን ፡ ተራራ ፡
የሚወጉ ፡ የአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ብዛት ፡ ይሆናል ።
፱ ተደነቁ ፡ ደንግጡም ፤ ተጨፈኑም ፡ ዕውሮ
ችም ፡ ሁኑ ፤ በወይን ፡ ጠጅ ፡ አይሁን ፡ እንጂ ፡
ሰክሩ ፤ በሚያሰክር ፡ መጠጥ ፡ አይሁን ፡ እንጂ ፡
፲ ተንገደገዱ ። እግዚአብሔር ፡ የእንቅልፍ ፡ መን
ፈስ ፡ አፍስሶባችኋል ፡ ዓይኖቻችሁን ፡ ነቢያት
ንም ፡ ጨፍኖባችኋል ፡ ራሶቻችሁን ፡ ባለ ፡ ራእ
፲፩ ዮችን ፡ ሸፍኖባችኋል ። ራእዩም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡
ታተመ ፡ መጽሐፍ ፡ ቃል ፡ ሆኖባችኋል ፤ ማን
በብንም ፡ ለሚያውቅ ፡— ይህን ፡ አንብብ ፡
ብለው ፡ በሰጡት ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡— ታትሞአ
፲፪ ልና ፡ አልችልም ፡ ይላቸዋል ፤ ደግሞም ፡ መጽ
ሐፉን ፡ ማንበብን ፡ ለማያውቅ ፡— ይህን ፡ አን
ብብ ፡ ብለው ፡ በሰጡት ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡— ማን
በብ ፡ አላውቅም ፡ ይላቸዋል ።
፲፫ ጌታም ፡— ይህ ፡ ሕዝብ ፡ በአፉ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡
ይቀርባልና ÷ በከንፈሮቹም ፡ ያከብረኛልና ÷
ልቡ ፡ ግን ፡ ከእኔ ፡ የራቀ ፡ ነውና ÷ በሰዎች ፡
ሥርዓትና ፡ ትምህርት ፡ ብቻ ፡ ይፈራኛልና ፡
፲፬ ስለዚህ ÷ እነሆ ÷ ድንቅ ፡ ነገርን ፡ በዚህ ፡ ሕዝብ ፡
መካከል ÷ ድንቅ ፡ ነገርን ፡ ተአምራትንም ÷
እንደ ፡ ገና ፡ አደርጋለሁ ፤ የጥበበኞችም ፡ ጥበብ ፡
ትጠፋለች ÷ የአስተዋዮችም ፡ ማስተዋል ፡ ትሰ
ወራለች ።
፲፭ ምክራቸውን ፡ ጥልቅ ፡ አድርገው ፡ ከእግዚ
አብሔር ፡ ለሚሰውሩ ÷ ሥራቸውንም ፡ በጨ
ለማ ፡ ውስጥ ፡ አድርገው ፡— ማን ፡ ያየናል ?
ወይስ ፡ ማን ፡ ያውቀናል ? ለሚሉ ፡ ወዮላቸው !
፲፮ ይህ ፡ የእናንተ ፡ ጠማምነት ፡ ነው ፤ እንደ ፡
ሸክላ ፡ ሠሪ ፡ ጭቃ ፡ የምትቈጠሩ ፡ አይደላች

ሁምን ? በውኑ ፡ ሥራ ፡ ሠሪውን ፡— አልሠ
ራኸኝም ፡ ይለዋልን ? ወይስ ፡ የተደረገው ፡
አድራጊውን ፡— አታስተውልም ፡ ይለዋለን ?
፲፯ ሊባኖስ ፡ እንደ ፡ ፍሬያማ ፡ እርሻ ፡ ሊለወጥ ፡
ፍሬያማውም ፡ እርሻ ፡ እንደ ፡ ዱር ፡ ሊቈጠር ፡
፲፰ ጥቂት ፡ ዘመን ፡ የቀረ ፡ አይደለምን ? በዚያም ፡
ቀን ፡ ደንቆሮች ፡ የመጽሐፍን ፡ ቃል ፡ ይሰማሉ ÷
የዕውሮችም ፡ ዓይኖች ፡ ከጭጋግና ፡ ከጨለማ ፡
፲፱ ተለይተው ፡ ያያሉ ። የዋሃን ፡ ደስታቸውን ፡
በእግዚአብሔር ፡ ያበዛሉ ÷ በሰዎች ፡ መካከል ፡
ያሉ ፡ ችግረኞችም ፡ ሐሤትን ፡ በእስራኤል ፡
፳ ቅዱስ ፡ ያደርጋሉ ። ጨካኙ ፡ ሰው ፡ አልቆአልና ÷
ፌዘኛውም ፡ ጠፍቶአልና ÷ ለኃጢአትም ፡
፳፩ የደፈጡ ፡ ሁሉ ፡ ይቈረጣሉና ፤ እነዚህም ፡
ሰውን ፡ በነገር ፡ በደለኛ ፡ የሚያደርጉ ÷ በበ
ርም ፡ ለሚገሥጸው ፡ አሽክላ ፡ የሚያኖሩ ÷ ጻድ
ቁንም ፡ በከንቱ ፡ ነገር ፡ የሚያስቱ ፡ ናቸው ።
፳፪ ስለዚህ ፡ አብርሃምን ፡ የተቤዠ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ስለ ፡ ያዕቆብ ፡ ቤት ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ያዕቆብ ፡ አሁን ፡ አያፍርም ÷ ፊቱም ፡ አሁን ፡
፳፫ አይለወጥም ። ነገር ፡ ግን ፡ የእጄን ፡ ሥራ ፡ ልጆ
ቹን ፡ በመካከሉ ፡ ባያቸው ፡ ጊዜ ፡ ስሜን ፡ ይቀ
ድሳሉ ፤ የያዕቆብንም ፡ ቅዱስ ፡ ይቀድሳሉ ÷
፳፬ የእስራኤልንም ፡ አምላክ ፡ ይፈራሉ ። በመን
ፈስም ፡ የሳቱ ፡ ማስተዋልን ፡ ያውቃሉ ÷ የሚ
ያጕረመርሙም ፡ ትምህርትን ፡ ይቀበላሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

፩ ለዓመፀኞች ፡ ልጆች ፡ ወዮላቸው ! ይላል ፡
እግዚአብሔር ፤ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ያልሆነን ፡ ምክር ፡
ይመክራሉ ÷ ኃጢአትንም ፡ በኃጢአት ፡ ላይ ፡
ይጨምሩ ፡ ዘንድ ፡ ከመንፈሴ ፡ ዘንድ ፡ ያልሆነ
፪ ውን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ያደርጋሉ ። ከአፌም ፡ ነገ
ርን ፡ ሳይጠይቁ ፡ በፈርዖን ፡ ኃይል ፡ ይጸኑ ፡
ዘንድ ፡ በግብጽም ፡ ጥላ ፡ ይታመኑ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡
፫ ግብጽ ፡ እንዲወርዱ ፡ ይሄዳሉ ። ስለዚህ ፡ የፈ
ርዖን ፡ ኃይል ፡ እፍረት ፡ በግብጽም ፡ ጥላ ፡ መታ
፬ መን ፡ ስድብ ፡ ይሆንባችኋል ። አለቆች ፡ ምንም ፡
በጣኔዎስ ፡ ቢሆኑ ÷ መልእክተኞችም ፡ ምንም ፡
፭ ወደ ፡ ሓኔስ ፡ ቢደርሱ ÷ ሁላቸው ፡ ይጠቅሙአ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ ስለማይችሉ ÷ እፍረትና ፡ ስድብ ፡
እንጂ ፡ ረድኤትና ፡ ረብ ፡ ስለማይሆኑ ፡ ሕዝብ ፡
ያፍራሉ ።
፮ በደቡብ ፡ ስላሉ ፡ እንስሶች ፡ የተነገረ ፡ ሸክም ።
ተባትና ፡ እንስት ፡ አንበሳ ፡ እፉኝትም ፡ ነዘር ፡
እባብም ፡ በሚወጡበት ፡ በመከራና ፡ በጭን
ቀት ፡ ምድር ፡ በኩል ፡ ብልጥግናቸውን ፡ በአህ
ዮች ፡ ጫንቃ ፡ ላይ ፡ መዛግብቶቻቸውንም ፡ በግ
መሎች ፡ ሻኛ ፡ ላይ ፡ እየጫኑ ፡ ወደማይጠቅሙ
፯ አቸው ፡ ሕዝብ ፡ ይሄዳሉ ። የግብጽ ፡ እርዳታ ፡
ከንቱና ፡ ምናምን ፡ ነው ፤ ስለዚህ ፡ ስሙን ፡—
በቤት ፡ የሚቀመጥ ፡ ረዓብ ፡ ብዬ ፡ ጠርቼዋለሁ ።
፰ አሁንም ፡ ሂድ ÷ ለሚመጣውም ፡ ዘመን ፡ ለዘላ
ለም ፡ እንዲሆን ፡ በሰሌዳ ፡ ላይ ፡ በመጽሐፍም ፡
ውስጥ ፡ ጻፍላቸው ። ዓመፀኛ ፡ ወገንና ፡ የእግ ፱
ዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ለመስማት ፡ የማይወድዱ ፡
የሐሰት ፡ ልጆች ፡ ናቸውና ፤ ባለ ፡ ራእዮችን ፡— ፲
አትመልከቱ ፡ ይላሉ ÷ ነቢያትንም ፡— ጣፋጩ
ንና ፡ አታላዩን ፡ ነገር ፡ እንጂ ፡ ቅኑን ፡ ነገር ፡
አትንገሩን ፤ ከመንገድ ፡ ፈቀቅ ፡ በሉ ÷ ከጐዳ ፲፩
ናውም ፡ ዘወር ፡ በሉ ÷ የእስራኤልንም ፡ ቅዱስ ፡
ከእኛ ፡ ዘንድ ፡ አስወግዱ ፡ ይሉአቸዋል ። ስለ ፲፪
ዚህ ፡ የእስራኤል ፡ ቅዱስ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ይህችን ፡ ቃል ፡ አቃልላችኋልና ÷ በግፍና ፡
በጠማምነት ፡ ታምናችኋልና ÷ በእርሱም ፡ ተደ
ግፋችኋልና ፡ ስለዚህ ፡ ይህ ፡ በደል ፡ አዘብዝቦ ፡ ፲፫
ለመፍረስ ፡ እንደ ፡ ቀረበ ÷ አፈራረሱም ፡ ፈጥኖ ፡
ድንገት ፡ እንደሚመጣ ፡ እንደ ፡ ረጅም ፡ ቅጥር ፡
ይሆንባችኋል ። የሸክለኛ ፡ ማድጋ ፡ እንደሚ ፲፬
ሰበር ፡ ይሰብረዋል ÷ ሳይራራም ፡ ያደቅቀዋል ፤
ከስባሪውም ፡ እሳት ፡ ከማንደጃ ፡ የሚወስዱ
በት ፡ ወይም ፡ ውኃ ፡ ከጕድጓድ ፡ የሚቀዱበት ፡
ገል ፡ አይገኝም ።
የእስራኤል ፡ ቅዱስ ÷ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፲፭
እንዲህ ፡ ይላልና ፡— በመመለስና ፡ በማረፍ ፡
ትድናላችሁ ፤ በጸጥታና ፡ በመታመን ፡ ኃይል ፡
ይሆንላችኋል ፤ እናንተም ፡ እንቢ ፡ አላችሁ ÷
ነገር ፡ ግን ፡— በፈረስ ፡ ላይ ፡ ተቀምጠን ፡ እንሸ ፲፮
ሻለን ፡ እንጂ ፡ እንዲህ ፡ አይሆንም ፡ አላችሁ ÷
ስለዚህም ፡ ትሸሻላችሁ ፤ ደግሞም ፡— በፈጣን ፡
ፈረስ ፡ ላይ ፡ እንቀመጣለን ፡ አላችሁ ÷ ስለዚ
ህም ፡ የሚያሳድዱአችሁ ፡ ፈጣኖች ፡ ይሆናሉ ።
ከአንድ ፡ ሰው ፡ ዛቻ ፡ የተነሣ ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ፲፯
ይሸሻሉ ፤ እናንተም ፡ በተራራ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ እን
ዳለ ፡ ምሰሶ ÷ በኮረብታም ፡ ላይ ፡ እንዳለ ፡ ምል
ክት ፡ ሆናችሁ ፡ እስክትቀሩ ፡ ድረስ ÷ ከአምስት ፡
ሰዎች ፡ ዛቻ ፡ የተነሣ ፡ ትሸሻላችሁ ። እግዚአ ፲፰
ብሔርም ፡ የፍርድ ፡ አምላክ ፡ ነውና ፡ ስለዚህ ፡
እግዚአብሔር ፡ ይራራላችሁ ፡ ዘንድ ፡ ይታገ
ሣል ÷ ይምራችሁም ፡ ዘንድ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ፤
እርሱን ፡ በመተማመን ፡ የሚጠባበቁ ፡ ሁሉ ፡
ብፁዓን ፡ ናቸው ።
በኢየሩሳሌም ፡ ውስጥ ፡ በጽዮን ፡ የምትኖሩ ፡ ፲፱
ሕዝብ ፡ ሆይ ÷ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አታለቅ
ስም ፤ በጩኸትም ፡ ድምፅ ፡ ይራራልሃል ÷ በሰ
ማህም ፡ ጊዜ ፡ ይመልስልሃል ። ጌታም ፡ የጭ ፳
ንቀትን ፡ እንጀራና ፡ የመከራን ፡ ውኃ ፡ ቢሰጥ
ህም ፡ አስተማሪህ ፡ እንግዲህ ፡ ከአንተ ፡ አይሰ
ወርም ፤ ዓይኖችህ ፡ ግን ፡ አስተማሪህን ፡ ያያሉ ÷
ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ ፈቀቅ ፡ ብትል ፡ ፳፩
ጆሮችህ ፡ በኋላህ ፡— መንገዱ ፡ ይህች ፡ ናት ፡
በእርስዋም ፡ ሂድ ፡ የሚለውን ፡ ቃል ፡ ይሰማሉ ።
በብርም ፡ የተለበጡትን ፡ የተቀረጹትን ፡ ምስሎ ፳፪
ችህን ፡ በወርቅም ፡ የተለበጡትን ፡ ቀልጠው ፡
የተሠሩትን ፡ ምስሎችህን ፡ ታረክሳለህ ፤ እንደ ፡
ርኩስም ፡ ነገር ፡ ትጥላቸዋለህ ፡— ወግዱ ፡ ትላ
ቸውማለህ ። በምድርም ፡ ለተዘራው ፡ ዘርህ ፡ ፳፫
ዝናብ ፡ ይሰጣል ÷ ከምድርም ፡ ፍሬ ፡ የሚ

ወጣ ፡ እንጀራ ፡ ወፍራምና ፡ ብዙ ፡ ይሆናል ።
በዚያም ፡ ቀን ፡ ከብቶችህ ፡ በሰፊ ፡ መስክ ፡ ይሰ
፳፬ ማራሉ ፤ መሬትንም ፡ የሚያርሱ ፡ በሬዎችና ፡
አህዮች ፡ በመንሽና ፡ በወንፊት ፡ የነጻውን ፡
ጨው ፡ ጨው ፡ የሚለውን ፡ ገፈራ ፡ ይበላሉ ።
፳፭ በታላቅም ፡ እልቂት ፡ ቀን ፡ ግንቦች ፡ በወደቁ ፡
ጊዜ ፡ በረጅሙ ፡ ተራራ ፡ ሁሉ ፡ ከፍ ፡ ባለውም ፡
ኮረብታ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ወንዞችና ፡ የውኃ ፡ ፈሳ
፳፮ ሾች ፡ ይሆናሉ ። እግዚአብሔርም ፡ የሕዝቡን ፡
ስብራት ፡ በጠገነ ፡ ዕለት ፥ መቅሠፍቱ ፡ የቈሰለ
ውንም ፡ በፈወሰ ፡ ዕለት ፥ የጨረቃ ፡ ብርሃን ፡
እንደ ፡ ፀሐይ ፡ ብርሃን ፥ የፀሐይም ፡ ብርሃን ፡
እንደ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ብርሃን ፡ ሰባት ፡ እጥፍ ፡
ይሆናል ።

፳፯ እነሆ ፥ የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ከሚነድድ ፡
ቍጣ ፡ ከሚትጐለጐልም ፡ ጢስ ፡ ጋር ፡ ከሩቅ ፡
ይመጣል ፤ ከንፈሮቹም ፡ ቍጣን ፡ የሞሉ ፡
ናቸው ፥ ምላሱም ፡ እንደምትበላ ፡ እሳት ፡ ናት ፤
፳፰ እስትንፋሱም ፡ አሕዛብን ፡ በእጥፊ ፡ ወንፊት ፡
ሊነፋቸው ፡ እንደሚያጥለቀልቅ ፡ እስከ ፡ አንገ
ትም ፡ እንደሚደርስ ፡ ወንዝ ፡ ነው ፥ በሕዝብም ፡
፳፱ መንጋጋ ፡ የሚያስት ፡ ልጓም ፡ ይሆናል ። ዝማሬ ፡
በተቀደሰች ፡ የዐውደ ፡ ዓመት ፡ ሌሊት ፡ እንደ
ሚሆን ፡ ዝማሬ ፡ ይሆንላችኋል ፤ ወደ ፡ እግዚ
አብሔርም ፡ ተራራ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ አምባ ፡
ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ እንቢልታ ፡ ይዞ ፡ እንደሚ
ሄድ ፡ ሰው ፡ የልብ ፡ ደስታ ፡ ይሆንላችኋል ።
፴ እግዚአብሔርም ፡ ክቡር ፡ ድምፁን ፡ ያሰማል ፥
የክንዱንም ፡ መውረድ ፡ በሚነድድ ፡ ቍጣ
ውና ፡ በምትበላ ፡ እሳት ፡ ነበልባል ፡ በዐውሎ ፡
ነፋስም ፡ በወጨፎም ፡ በበረዶ ፡ ጠጠርም ፡ ይገ
፴፩ ልጣል ። አሦርም ፡ በበትር ፡ ከመታው ፡ ከእ
ግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ የተነሣ ፡ ይደነግጣል ።
፴፪ እግዚአብሔር ፡ በላዩ ፡ የሚያወርድበት ፡ የታዘ
ዘበቱ ፡ የበትር ፡ ድብደባ ፡ ሁሉ ፡ በከበሮና ፡ በመ
ሰንቆ ፡ ይሆናል ፤ በጦርነትም ፡ ክንዱን ፡ አን
፴፫ ሥቶ ፡ ይዋጋቸዋል ። ከቀድሞም ፡ ጀምሮ ፡
የማቃጠያ ፡ ስፍራ ፡ ተዘጋጅታለች ፥ ለንጉሥም ፡
ተበጅታለች ፤ ጥልቅና ፡ ሰፊም ፡ አድርጎአታል ፤
እሳትና ፡ ብዙ ፡ ማገዶ ፡ ተከምሮአል ፤ የእግዚ
አብሔርም ፡ እስትንፋስ ፡ እንደ ፡ ዲን ፡ ፈሳሽ ፡
ያቃጥለዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፩ ።

፩ ስለ ፡ እርዳታ ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ለሚወርዱ ፡ በፈ
ረሶችም ፡ ለሚደገፉ ፥ ስለ ፡ ብዛታቸውም ፡ በሰረ
ገሎች ፥ እጅግ ፡ ብርቱዎችም ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ በፈ
ረሰኞች ፡ ለሚታመኑ ፥ ወደ ፡ እስራኤልም ፡
ቅዱስ ፡ ለማይመለከቱ ፡ እግዚአብሔርንም ፡
፪ ለማይፈልጉ ፡ ወዮላቸው ! እርሱ ፡ ግን ፡ ደግሞ ፡
ጠቢብ ፡ ነው ፥ ክፉንም ፡ ነገር ፡ ያመጣል ፥ ቃሉ
ንም ፡ አይመልስም ፥ በክፉም ፡ አድራጊዎች ፡
ቤት ፡ ላይ ፡ በደልንም ፡ በሚሠሩ ፡ ረዳት ፡ ላይ ፡
፫ ይነሣል ። ግብጻውያን ፡ ሰዎች ፡ እንጂ ፡ አም
ላክ ፡ አይደሉም ፥ ፈረሶቻቸውም ፡ ሥጋ ፡
እንጂ ፡ መንፈስ ፡ አይደሉም ፤ እግዚአብሔ
ርም ፡ እጁን ፡ በዘረጋ ፡ ጊዜ ፥ ረጂው ፡ ይሰናከ
ላል ፡ ተረጂውም ፡ ይወድቃል ፥ ሁሉም ፡ በአ
ንድ ፡ ላይ ፡ ይጠፋሉ ።

፬ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ ይለኛልና ፡—
አንበሳ ፡ ወይም ፡ የአንበሳ ፡ ደቦል ፡ በንጥቂያው ፡
ላይ ፡ ሲያገሣ ፥ ብዙ ፡ እረኞች ፡ ቢከማቹበት ፡
ከቃላቸው ፡ እንደማይፈራ ፡ ከድምፃቸውም ፡
እንደማይዋረድ ፥ እንዲሁ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፡ በጽዮን ፡ ተራራና ፡ በኮረብ
፭ ታዋ ፡ ላይ ፡ ይዋጋ ፡ ዘንድ ፡ ይወርዳል ። እንደ
ሚበርር ፡ ወፍ ፡ እንዲሁ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ይጋርዳታል ፤ ይከ
ልላታል ፥ ይታደጋታል ፥ አልፎም ፡ ያድና
፮ ታል ። እናንተ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥
አጥብቃችሁ ፡ ወደ ፡ ዐመፃችሁበት ፡ ተመለሱ ።
፯ በዚያም ፡ ቀን ፡ እያንዳንዳቸው ፡ እጆቻቸው ፡
ለኃጢአት ፡ የሠሩላቸውን ፡ የብሩንና ፡ የወር
፰ ቁን ፡ ጣዖቶቻቸውን ፡ ይጥላሉ ። አሦርም ፡
የሰው ፡ በልሆነ ፡ ሰይፍ ፡ ይወድቃል ፥ የሰውም ፡
ያልሆነ ፡ ሰይፍ ፡ ይበላዋል ፤ ከሰይፍም ፡ ይሸሻል ፡
፱ ጐበዛዝቱም ፡ ገባሮች ፡ ይሆናሉ ። አምባው ፡ ከፍ
ርሃት ፡ የተነሣ ፡ ያልፋል ፡ መሳፍንቱም ፡ ከዓላ
ማው ፡ የተነሣ ፡ ይደነግጣሉ ፥ ይላል ፡ እሳቱ ፡
በጽዮን ፡ እቶኑም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሆነ ፡ እግ
ዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

፩ እነሆ ፥ ንጉሥ ፡ በጽድቅ ፡ ይነግሣል ፥ መሳፍ
፪ ንትም ፡ በፍርድ ፡ ይገዛሉ ። ሰውም ፡ ከነፋስ ፡
እንደ ፡ መሸሸጊያ ፡ ከዐውሎ ፡ ነፋስም ፡ እንደ ፡
መጠጊያ ፥ በጥም ፡ በታም ፡ እንደ ፡ ወንዝ ፡
ፈሳሽ ፥ በበረሀም ፡ አገር ፡ እንደ ፡ ትልቅ ፡ ድን
፫ ጋይ ፡ ጥላ ፡ ይሆናል ። የሚያዩትም ፡ ሰዎች ፡
ዓይኖች ፡ አይጨፈኑም ፥ የሚሰሙትም ፡
፬ ጆሮች ፡ ያደምጣሉ ። ጥንቃቄ ፡ የሌላቸው ፡
ሰዎች ፡ ልብ ፡ እውቀትን ፡ ታስተውላለች ፥ የተ
ብታቡችም ፡ ምላስ ፡ ደኅና ፡ አድርጋ ፡ ትናገራ
፭ ለች ። ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ሰነፍ ፡ ከበርቴ ፡
ተብሎ ፡ አይጠራም ፥ ንፉግም ፡ ለጋስ ፡ አይባ
፮ ልም ። ሰነፍ ፡ ግን ፡ ስንፍናን ፡ ይናገራል ፥
ልቡም ፡ ዝንጉነትን ፡ ይፈጽም ፡ ዘንድ ፡ በእግ
ዚአብሔርም ፡ ላይ ፡ ስሕተትን ፡ ይናገር ፡ ዘንድ ፥
የተራበችውንም ፡ ሰውነት ፡ ባዶ ፡ ያደርግ ፡
ዘንድ ፡ ከተጠማም ፡ ሰው ፡ መጠጥን ፡ ይቈርጥ ፡
፯ ዘንድ ፡ በደልን ፡ ይሠራል ። የንፉግም ፡ ዕቃ ፡
ክፉ ፡ ናት ፤ ችግረኛ ፡ ቅን ፡ ነገርን ፡ በተናገረ ፡
ጊዜ ፡ እንኳ ፡ እርሱ ፡ በሐሰት ፡ ቃል ፡ ድሀውን ፡
፰ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ ክፉን ፡ አሳብ ፡ ያስባል ። ከበ
ርቴ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ለመከበር ፡ ያስባል ፥ በመከ
በርም ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ።
፱ እናንተ ፡ ዓለመኞች ፡ ሴቶች ፡ ሆይ ፥ ተነሡ ፡
ድምፄንም ፡ ስሙ ፤ እናንተ ፡ ተማምናችሁ ፡

የምትቀመጡ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ ንግግ
፲ ሬን ፡ አድምጡ ። እናንተ ፡ ተማምናችሁ ፡ የም
ትቀመጡ ፡ ሴቶች ፡ ሆይ ፥ ወይንን ፡ መቍረጥ ፡
ይጠፋልና ፥ ፍሬም ፡ ማከማቸት ፡ አይመጣምና ፡
ከዓመትና ፡ ከጥቂት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ትንቀጠቀጣ
፲፩ ላችሁ ። እናንተ ፡ ዓለመኞች ፡ ሴቶች ፡ ሆይ ፥
ተጠንቀቁ ፤ ተማምናችሁም ፡ የምትቀመጡ ፡
ሆይ ፥ ተንቀጥቀጡ ፤ ልብሳችሁን ፡ አውልቁ ፥
ዕራቁታችሁን ፡ ሁኑ ፥ ወገባችሁንም ፡ በማቅ ፡
፲፪ ታጠቁ ። ስለ ፡ ተወደደችውም ፡ እርሻ ፡ ስለሚ
ያፈራውም ፡ ወይን ፡ ደረታችሁን ፡ ድቁ ።
፲፫ በሕዝቤ ፡ ምድር ፡ ላይ ፥ በደስታ ፡ ከተማ ፡
ባሉት ፡ በደስታ ፡ ቤቶች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እሾህና ፡
፲፬ ኵርንችት ፡ ይወጣባቸዋል ፤ አዳራሹ ፡ ወና ፡
ትሆናለችና ፥ የብዙ ፡ ሰውም ፡ ከተማ ፡ ትለቀቃ
ለችና ፥ አምባውና ፡ ግንቡም ፡ ለዘላለም ፡ ዋሻ ፥
የምድረ ፡ በዳም ፡ አህያ ፡ ደስታ ፥ የመንጎችም ፡
፲፭ ማሰማርያ ፡ ይሆናልና ። ይህም ፥ መንፈስ ፡ ከላይ ፡
እስኪፈስስልን ፥ ምድረ ፡ በዳውም ፡ ፍሬያማ ፡
እርሻ ፡ እስኪሆን ፥ ፍሬያማውም ፡ እርሻ ፡ ዱር ፡
ተብሎ ፡ እስኪቈጠር ፡ ድረስ ፡ ይሆናል ።
፲፮ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ፍርድ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ይኖ
ራል ፥ ጽድቅም ፡ በፍሬያማው ፡ እርሻ ፡ ያድራል ።
፲፯ የጽድቅም ፡ ሥራ ፡ ሰላም ፥ የጽድቅም ፡ ፍሬ ፡
፲፰ ለዘላለም ፡ ጸጥታና ፡ መታመን ፡ ይሆናል ። ሕዝ
ቤም ፡ በሰላም ፡ ማደሪያ ፡ በታመነም ፡ ቤት ፡
፲፱ በጸጥተኛ ፡ ማረፊያ ፡ ይቀመጣል ። በረዶ ፡ ግን ፡
በዱር ፡ ላይ ፡ ይወርዳል ፥ ከተማም ፡ ፈጽማ ፡
፳ ትዋረዳለች ። እናንተ ፡ የበሬና ፡ የአህያ ፡ እግር ፡
እየነዳችሁ ፡ በውኃ ፡ ሁሉ ፡ አጠገብ ፡ የምት
ዘሩ ፡ ብፁዓን ፡ ናችሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፫ ።

፩ አንተ ፡ ሳትጠፋ ፡ የምታጠፋ ፥ በአንተም ፡
ላይ ፡ ወንጀል ፡ ሳይደረግ ፡ ወንጀል ፡ የምታደ
ርግ ፡ ወዮልህ ! ማጥፋትን ፡ በተውህ ፡ ጊዜ ፡
ትጠፋለህ ፤ መወንጀልንም ፡ በተውህ ፡ ጊዜ ፡ ይወ
፪ ነጅሉሃል ። አቤቱ ፥ ማረን ፤ አንተን ፡ ተማምነ
ናል ፤ ጥዋት ፡ ጥዋት ፡ ክንድ ፡ በመከራም ፡ ጊዜ ፡
፫ ማዳን ፡ ሁነን ። ከፍጅት ፡ ድምፅ ፡ ወገኖች ፡ ሸሹ ፥
፬ በመነሣትህም ፡ አሕዛብ ፡ ተበተኑ ። አንበጣ ፡ እን
ደሚሰበስብ ፡ ምርኮአችሁ ፡ ትሰበሰባለች ፥ ኩብ
ኩባም ፡ እንደሚዘልል ፡ ሰዎች ፡ ይዘልሉበታል ።
፭ እግዚአብሔር ፡ በአርያም ፡ ተቀምጦአልና ፡
ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ፤ ጽዮንን ፡ በፍርድና ፡ በጽድቅ ፡
፮ ሞላት ። የዘመንህም ፡ ጸጥታ ፥ የመድኃኒት ፡
ብዛት ፥ ጥበብና ፡ እውቀት ፡ ይሆናል ፤ እግዚ
አብሔርን ፡ መፍራት ፡ መዝገቡ ፡ ነው ።
፯ እነሆ ፥ ኃይለኞቻቸው ፡ በሜዳ ፡ ይጮኻሉ ፤
የሰላም ፡ መልእክተኞች ፡ መራራ ፡ ልቅሶ ፡ ያለ
፰ ቅሳሉ ። መንገዶች ፡ ባድማ ፡ ሆኑ ፥ ተላላፊም ፡
ቀረ ፤ እርሱም ፡ ቃል ፡ ኪዳንን ፡ አፈረሰ ፡ ከተ
ሞችንም ፡ ናቀ ፡ ሰውንም ፡ አልተመለከተም ።

፱ ምድሪቱ ፡ አለቀሰች ፡ ከሳችም ፤ ሊባኖስ ፡ አፈረ ፡
ጠወለገም ፤ ሳሮን ፡ እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሆነ ፤
ባሳንና ፡ ቀርሜሎስ ፡ ቅጠላቸውን ፡ አረገፉ ።
፲ አሁን ፡ እነሣለሁ ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤
አሁን ፡ እከበራለሁ ፤ አሁን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እላ
፲፩ ለሁ ። ገለባን ፡ ትፀንሳላችሁ ፥ እብቅንም ፡ ትወ
ልዳላችሁ ፤ እስትንፋሳችሁ ፡ የምትበላችሁ ፡
፲፪ እሳት ፡ ናት ። አሕዛብም ፡ እንደ ፡ ተቃጠለ ፡
ኖራ ፥ ተቈርጠም ፡ በእሳት ፡ እንደ ፡ ተቃጠለ ፡
እሾህ ፡ ይሆናሉ ።
፲፫ እናንተ ፡ በሩቅ ፡ ያላችሁ ፡ የሠራሁትን ፡
ስሙ ፥ እናንተም ፡ በቅርብ ፡ ያላችሁ ፡ ኃይሌን ፡
፲፬ እወቁ ። በጽዮን ፡ ያሉ ፡ ኃጢአተኞች ፡ ፈሩ ፤
መንቀጥቀጥ ፡ ዝንጉዎቹን ፡ ያዘ ፤ ከምትበላ ፡
እሳት ፡ ጋር ፡ መኖርን ፡ የሚችል ፡ ከእኛ ፡ ማን ፡
አለ ? ለዘላለምም ፡ ከምትነድድ ፡ እሳት ፡ ጋር ፡
፲፭ መኖርን ፡ የሚችል ፡ ከእኛ ፡ ማን ፡ አለ ? በጽ
ድቅ ፡ የሚሄድ ፡ ቅን ፡ ነገርንም ፡ የሚናገር ፥
በሽንገላ ፡ የሚገኝ ፡ ትርፍን ፡ የሚንቅ ፥ መማ
ለጃን ፡ ከመጨበጥ ፡ እጁን ፡ የሚያራግፍ ፥
ደም ፡ ማፍሰስን ፡ ከመስማት ፡ ጆሮቹን ፡ የሚያ
ደናቍር ፥ ክፋትንም ፡ ከማየት ፡ ዓይኖቹን ፡
፲፮ የሚጨፍን ፡ ነው ። እርሱ ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡ ስፍራ ፡
ይቀመጣል ፤ ጠንካራ ፡ አምባ ፡ መጠጊያው ፡
ይሆናል ፤ እንጀራም ፡ ይሰጠዋል ፥ ውኃውም ፡
የታመነች ፡ ትሆናለች ።
፲፯ ዓይኖችህ ፡ ንጉሥን ፡ በውበቱ ፡ ያዩታል ፤ እነ
ርሱም ፡ በሩቅ ፡ ያለች ፡ ምድርን ፡ ያዩአታል ።
፲፰ ልብህም ፡— ጸሐፊ ፡ ወዴት ፡ አለ ? መዛኙስ ፡
ወዴት ፡ አለ ? ግንቦቹንስ ፡ የቈጠረ ፡ ወዴት ፡
አለ ? ብሎ ፡ የሚያስፈራ ፡ ነገር ፡ ያስባል ።
፲፱ ጨካኙን ፡ ሕዝብ ፥ ቋንቋው ፡ ለማስተዋል ፡
ጥልቅ ፡ የሆነውንና ፡ አንደበቱ ፡ ለማስተዋል ፡
፳ ጸያፍ ፡ የሆነውን ፡ ሕዝብ ፥ አታይም ። የበዓላ
ችንን ፡ ከተማ ፡ ጽዮንን ፡ ተመልከት ፤ ዓይኖ
ችህ ፡ የሰላም ፡ ማደሪያ ፥ ካስማውም ፡ ለዘላ
ለም ፡ የማይነቀል ፡ አውታሩም ፡ ሁሉ ፡ የማይ
በጠስ ፥ የማይወገድ ፡ ድንኳን ፡ የሆነውን ፡ ኢየ
፳፩ ሩሳሌምን ፡ ያያሉ ። እግዚአብሔር ፡ በዚያ ፡
የሰፋ ፡ ወንዞችና ፡ የመስኖች ፡ ስፍራ ፡ ሆኖ ፡
ከእኛ ፡ ጋር ፡ በግርማ ፡ ይሆናል ፤ የሚቀዘፋ ፡
መርከቦች ፡ አይገቡበትም ፥ ታላላቆችም ፡ መር
፳፪ ከቦች ፡ አያልፉበትም ። እግዚአብሔር ፡ ፈራ
ጃችን ፡ ነው ፥ እግዚአብሔር ፡ ሕግን ፡ ሰጪያ
ችን ፡ ነው ፥ እግዚአብሔር ፡ ንጉሣችን ፡ ነው ፤
፳፫ እርሱ ፡ ያድነናል ። ገመዶችህ ፡ ላልተዋል ፥
ደቀላቸውንም ፡ አላጸኑም ፥ ሸራውንም ፡ መዘ
ርጋት ፡ አልቻሉም ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የብዙ ፡
ምርኮ ፡ ብዝበዛ ፡ ተከፈለ ፤ አንካሶች ፡ እንኳ ፡
፳፬ ብዝበዛውን ፡ በዘበዙ ። በዚያም ፡ የሚቀመጥ ፡—
ታምሜአለሁ ፡ አይልም ፥ በእርስዋም ፡ ለሚቀ
መጡ ፡ ሰዎች ፡ በደላቸው ፡ ይቅር ፡ ይባልላቸ
ዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፬ ።

፩፤ እናንተ ፡ አሕዛብ ፡ ሆይ ÷ ቅረቡ ÷ ስሙ ፤ እና
ንተ ፡ ወገኖች ፡ ሆይ ÷ አድምጡ ፤ ምድርና ፡
ሙላዋ ÷ ዓለምና ፡ ከእርስዋ ፡ የሚወጣ ፡ ሁሉ ፡
፪፤ ይስሙ ። የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በአሕዛብ ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ መዓቱም ፡ በሠራዊታቸው ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ ነው ፤ ፈጽሞ ፡ አጠፋቸው ÷ ለመታረ
፫፤ ድም ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ። ከእነርሱም ፡ የተገ
ደሉት ፡ ይጣላሉ ÷ የሬሳቸውም ፡ ግማት ፡ ይሸ
ታል ÷ ተራሮችም ፡ ከደማቸው ፡ የተነሣ ፡ ይር
፬፤ ሳሉ ። የሰማይም ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ ይበሰብ
ሳሉ ÷ ሰማያትም ፡ እንደ ፡ መጽሐፍ ፡ ጥቅልል ፡
ይጠቀለላሉ ÷ ከወይንና ፡ ከበለስም ፡ ቅጠል ፡
እንደሚረግፍ ፡ ሠራዊታቸው ፡ ሁሉ ፡ ይረግ
፭፤ ፋል ። ሰይፌ ፡ በሰማይ ፡ ሆና ፡ እስክትረካ ፡
ድረስ ፡ ጠጥታለች ፤ እነሆ ÷ በኤዶምያስና ፡ በረ
ገምሁት ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ ለፍርድ ፡ ትወርዳ
፮፤ ለች ። እግዚአብሔር ፡ መሥዋዕት ፡ በባሶራ ÷
ታላቅም ፡ እርድ ፡ በኤዶምያስ ፡ ምድር ፡ አለ
ውና ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰይፍ ፡ በደም ፡ ተሞል
ታለች ÷ በስብም ÷ በበግ ፡ ጠቦትና ፡ በፍየል ፡
ደምም ÷ በአውራም ፡ በግ ፡ ኵላሊት ፡ ስብ ፡
፯፤ ወፍራለች ። ጎሽ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ÷ ወይፈኖ
ችም ፡ ከኮርማዎች ፡ ጋር ፡ ይወድቃሉ ፤ ምድ
ራቸውም ፡ በደም ፡ ትረካለች ÷ አፈራቸውም ፡
በስብ ፡ ትወፍራለች ።
፰፤ የእግዚአብሔር ፡ የበቀሉ ፡ ቀን ÷ ስለ ፡ ጽዮ
፱፤ ንም ፡ ክርክር ፡ የብድራት ፡ ዓመት ፡ ነው ። የኤ
ዶምያስም ፡ ፈሳሾች ፡ ዝፍት ፡ ሆነው ፡ ይለወ
ጣሉ ÷ አፈርዋም ፡ ዲን ፡ ይሆናል ÷ መሬትዋም ፡
፲፤ የሚቃጠል ፡ ዝፍት ፡ ትሆናለች ። በሌሊትና ፡
በቀንም ፡ አትጠፋም ÷ ጢስዋም ፡ ለዘላለም ፡
ይወጣል ፤ ከትውልድ ፡ እስከ ፡ ትውልድም ፡
ድረስ ፡ ባድማ ፡ ሆና ፡ ትኖራለች ፤ ለዘላለም ፡
፲፩፤ ዓለም ፡ ማንም ፡ አያልፍባትም ። ጭልፊትና ፡
ጃርት ፡ ግን ፡ ይወርሱአታል ፤ ጕጕትና ፡ ቍራም ፡
ይኖሩባታል ፤ በላይዋም ፡ የመፍረስ ፡ ገመድና ፡
፲፪፤ የባዶነት ፡ ቱንቢ ፡ ይዘረጋባታል ። መሳፍንቶች
ዋን ፡ ወደ ፡ መንግሥት ፡ ይጠራሉ ÷ ነገር ፡ ግን ፡
ማንም ፡ አይገኝበትም ፤ አለቆችዋም ፡ ሁሉ ፡
፲፫፤ ምናምኖች ፡ ይሆናሉ ። በአዳራሾችዋም ፡ እሾህ ፡
በቅጥሮችዋም ፡ ሳማና ፡ አሜከላ ፡ ይበቅሉብ
ታል ፤ የቀበሮም ፡ ማደሪያና ፡ የሰጎን ፡ ስፍራ ፡
፲፬፤ ትሆናለች ። የምድረ ፡ በዳም ፡ አራዊት ፡ ከተ
ኵሎች ፡ ጋር ፡ ይገናኛሉ ÷ አጋንንትም ፡ እርስ ፡
በርሳቸው ፡ ይጠራራሉ ፤ ጅንም ፡ በዚያ ፡ ትኖ
፲፭፤ ራለች ፡ ለእርስዋም ፡ ማረፊያ ፡ ታገኛለች ። በዚ
ያም ፡ ዋሊያ ፡ ቤትዋን ፡ ትሠራለች ፡ እንቍላ
ልም ፡ ትጥላለች ፡ ትቀፈቅፈውማለች ፡ ልጆችዋ
ንም ፡ በጥላዋ ፡ ትሰበስባለች ፤ በዚያም ፡ ደግሞ ፡
አሞራዎች ፡ እያንዳንዳቸው ፡ ከባልንጀሮቻ
ቸው ፡ ጋር ፡ ይሰበሰባሉ ።
፲፮፤ በእግዚአብሔር ፡ መጽሐፍ ፡ ፈልጉ ፡ አንብ
ቡም ፤ አፌ ፡ አገዘአልና ÷ መንፈሱም ፡ ሰብስ
ቦአቸዋልና ፡ ከእነዚህ ፡ አንዲት ፡ አትጠፋም ÷
፲፯፤ ባልንጀራውንም ፡ የሚያጣ ፡ የለም ። እርሱም ፡
ዕጣ ፡ ጣለባቸው ÷ እጁም ፡ በገመድ ፡ ከፈለችላ
ቸው ፤ ለዘላለም ፡ ይገዙአታል ÷ ከትውልድም ፡
እስከ ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ ይቀመጡባታል ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፭ ።

፩፤ ምድረ ፡ በዳውና ፡ ደረቁ ፡ ምድር ፡ ደስ ፡ ይላ
ቸዋል ÷ በረሀውም ፡ ሐሤት ፡ ያደርጋል ፡ እንደ ፡
፪፤ ጽጌ ፡ ረዳም ፡ ያብባል ። እጅግ ፡ ያብባል ፡ በደ
ስታና ፡ በዝማሬ ፡ ሐሤትን ፡ ያደርጋል ፤ የሊባ
ኖስ ፡ ክብር ÷ የቀርሜሎስና ፡ የሳሮን ፡ ግርማ ፡
ይሰጠዋል ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ክብር ፡ የአ
ምላካችንንም ፡ ግርማ ፡ ያያሉ ።
፫፤ የደከሙትን ፡ እጆች ፡ አበርቱ ÷ የላሉትንም ፡
፬፤ ጕልበቶች ፡ አጽኑ ። ፈሪ ፡ ልብ ፡ ላላቸው ፡—
እነሆ ÷ አምላካችሁ ፡ በበቀል ፡ በእግዚአብሔ
ርም ፡ ብድራት ፡ ይመጣልና ÷ መጥቶም ፡ ያድ
ናችኋልና ፡ በርቱ ÷ አትፍሩ ፡ በሉአቸው ።
፭፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ የዕውሮች ፡ ዓይን ፡ ይገ
ለጣል ፡ የደንቆሮችም ፡ ጆሮ ፡ ይከፈታል ።
፮፤ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አንካሳ ፡ እንደ ፡ ሚዳቋ ፡ ይዘል
ላል ÷ የድዳም ፡ ምላስ ፡ ይዘምራል ፤ በምድረ ፡
በዳ ፡ ውኃ ÷ በበረሀም ፡ ፈሳሽ ፡ ይፈልቃልና ።
፯፤ ደረቂቱ ፡ ምድር ፡ ኵሬ ÷ የጥማት ፡ ምሬት ፡
የውኃ ፡ ምንጭ ፡ ትሆናለች ፤ ቀበሮ ፡ የተኛበት ፡
መኖሪያ ፡ ልምላሜና ፡ ሸምበቆ ፡ ደንገልም ፡
፰፤ ይሆንበታል ። በዚያም ፡ ጐዳናና ፡ መንገድ ፡
ይሆናል ፡ እርሱም ፡ የተቀደሰ ፡ መንገድ ፡ ይበ
ላል ፤ ንጹሐንም ፡ ያልሆኑ ፡ አያልፉበትም ÷
ለንጹሐን ፡ ግን ፡ ይሆናል ፤ ተላላፊዎችና ፡ ሰነ
፱፤ ፎች ፡ እንኳ ፡ አይስቱበትም ። አንበሳም ፡ አይ
ኖርበትም ÷ ነጣቂ ፡ አውሬም ፡ አይወጣበትም ÷
ከዚያም ፡ አይገኙም ፤ የዳኑት ፡ ግን ፡ በዚያ ፡
፲፤ ይሄዳሉ ፤ እግዚአብሔርም ፡ የተቤዣቸው ፡
ይመለሳሉ ፡ እየዘመሩም ፡ ወደ ፡ ጽዮን ፡ ይመ
ጣሉ ፤ የዘላለም ፡ ደስታ ፡ በራሳቸው ፡ ላይ ፡ ይሆ
ናል ፤ ሐሤትንና ፡ ደስታን ፡ ያገኛሉ ÷ ኀዘንና ፡
ትካዜም ፡ ይሸሻሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፮ ።

፩፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በንጉሡ ፡ በሕዝቅያስ ፡ በአ
ሥራ ፡ አራተኛው ፡ ዓመት ፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡
ሰናክሬም ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ወደ ፡ ተመሸጉት ፡
፪፤ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ወጥቶ ፡ ወሰዳቸው ። የአሦ
ርም ፡ ንጉሥ ፡ ራፋስቂስን ፡ ከብዙ ፡ ሠራዊት ፡
ጋር ፡ ከለኪሶ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ሕዝቅ
ያስ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ላከ ÷ እርሱም ፡ በአ
ጣቢው ፡ እርሻ ፡ መንገድ ፡ ባለችው ፡ በላይኛ
፫፤ ይቱ ፡ ኵሬ ፡ መስኖ ፡ አጠገብ ፡ ቆመ ። የቤቱም ፡
አዛዥ ፡ የኬልቅያስ ፡ ልጅ ፡ ኤልያቄም ፡ ጸሐፊ
ውም ፡ ሳምናስ ፡ ታሪክ ፡ ጸሐፊም ፡ የአሳፍ ፡
ልጅ ፡ ዮአስ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ወጡ ።

፬ ራፋስቂስም ፡ አላቸው ፡— ለሕዝቅያስ ፡ እንዲህ ፡ ብላችሁ ፡ ንገሩት ፡— ታላቁ ፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ይህ ፡ የምትታመንበት ፡ መተማመኛ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ፭ እኔ ፡— ለሰልፍ ፡ የሆነው ፡ ምክርህና ፡ ኃይልህ ፡ ከንቱ ፡ ነገር ፡ ነው ፡ እልሁ ፤ አሁንም ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ያመፀኸው ፡ በማን ፡ ተማምነህ ፡ ነው ? ፮ እነሆ ÷ በዚህ ፡ በተቀጠቀጠ ፡ በሸምበቆ ፡ በትር ፡ በግብጽ ፡ ትታመናለህ ፤ ሰው ፡ ቢመረኰዘው ፡ ተሰብሮ ፡ በእጁ ፡ ይገባል ፡ ያቈስለውማል ፤ የግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ፈርዖን ፡ ለሚታመኑበት ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ ነው ። ፯ አንተም ፡— በአምላካችን ፡ በእግዚአብሔር ፡ እንታመናለን ፡ ብትለኝ ÷ ሕዝቅያስ ፡ ይሁዳንና ፡ ኢየሩሳሌምን ፡— በዚህ ፡ መሠዊያ ፡ ፊት ፡ ስገዱ ፡ ብሎ ፡ የኮረብታ ፡ መስገጃዎቹንና ፡ መሠዊያዎቹን ፡ ያስፈረሰ ፡ ይህ ፡ አይደለምን ? ፰ አሁን ፡ እንግዲህ ፡ ከጌታዬ ፡ ከአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ጋር ፡ ተወራረድ ÷ የሚቀመጡባቸውንም ፡ ሰዎች ፡ ማግኘት ፡ ቢቻልህ ፡ እኔ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ፈረሶች ፡ እሰጥሃለሁ ። ፱ ስለ ፡ ሰረገሎችና ፡ ስለ ፡ ፈረሰኞች ፡ በግብጽ ፡ ስትታመን ÷ ከጌታዬ ፡ ባሪያዎች ፡ የሚያንሰውን ፡ የአንዱን ፡ አለቃ ፡ ፊት ፡ ትቃወም ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ይቻልሃል ? ፲ አሁንም ፡ በውኑ ፡ ያለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ ይህን ፡ አገር ፡ አጠፋ ፡ ዘንድ ፡ ወጥቻለሁን ? እግዚአብሔር ፡— ወደዚህ ፡ አገር ፡ ወጥተህ ፡ አጥፋው ፡ አለኝ ።

፲፩ ኤልያቄምና ፡ ሳምናስ ፡ ዮአስም ፡ ራፋስቂስን ፡— እኛ ፡ እንሰማለንና ፡ እባክህ ÷ በሶርያ ፡ ቋንቋ ፡ ለባሪያዎችህ ፡ ተናገር ፤ በቅጥርም ፡ ላይ ፡ ባለው ፡ ሕዝብ ፡ ጆሮ ፡ በአይሁድ ፡ ቋንቋ ፡ አትናገረን ፡ አሉት ። ፲፪ ራፋስቂስ ፡ ግን ፡— ጌታዬ ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ አንተና ፡ ወደ ፡ ጌታህ ፡ ልኮኛልን ? ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ኵሳቸውን ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ ሽንታቸውንም ፡ ይጠጡ ፡ ዘንድ ፡ በቅጥር ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ተቀመጡት ፡ ሰዎች ፡ አይደለምን ? አላቸው ። ፲፫ ራፋስቂስም ፡ ቆሞ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ በአይሁድ ፡ ቋንቋ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ጮኸ ፡— የታላቁን ፡ የአሦርን ፡ ንጉሥ ፡ ቃል ፡ ስሙ ። ፲፬ ንጉሡ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ያድናችሁ ፡ ዘንድ ፡ አይችልምና ፡ ሕዝቅያስ ፡ አያታልላችሁ ፤ ፲፭ ሕዝቅያስም ፡— እግዚአብሔር ፡ በእርግጥ ፡ ያድነናል ፡ ይህችም ፡ ከተማ ፡ በአሦር ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ አትሰጥም ፡ ብሎ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እንድትታመኑ ፡ አያድርጋችሁ ። ፲፮ ሕዝቅያስንም ፡ አትስሙ ፤ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ከእኔ ፡ ጋር ፡ ታረቁ ፡ ወደ ፡ እኔም ፡ ውጡ ፤ እያንዳንዳችሁም ፡ ከወይናችሁና ፡ ከበለሳችሁ ፡ ብሉ ÷ ከጕድጓዳችሁም ፡ ውኃ ፡ ጠጡ ፤ ፲፯ ይህም ፡ መጥቼ ፡ ምድራችሁን ፡ ወደምትመስለው ፡ ምድር ÷ እህልና ፡ የወይን ፡ ጠጅ ÷ እንጀራና ፡ ወይን ፡ ወዳለበት ፡ ምድር ፡ እስካፈልሳችሁ ፡ ድረስ ፡ ነው ። ፲፰ ሕዝቅያስም ፡— እግዚአብሔር ፡ ያድነናል ፡ ብሎ ፡ እንዳያታልላችሁ ፡ ተጠንቀቁ ። በውኑ ፡ የአሕዛብ ፡ አማልክት ፡ አገሮቻቸውን ፡ ከአሦር ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ አድነዋቸዋልን ? ፲፱ የሐማትና ፡ የአርፋድ ፡ አማልክት ፡ ወዴት ፡ አሉ ? የሴፈርዋይም ፡ አማልክት ፡ ወዴት ፡ አሉ ? ሰማርያን ፡ ከእጄ ፡ አድነዋታልን ? ፳ እግዚአብሔር ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ከእጄ ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ ከእነዚህ ፡ አገሮች ፡ አማልክት ፡ ሁሉ ፡ አገሩን ፡ ከእጄ ፡ ያዳነ ፡ ማን ፡ ነው ?

፳፩ እነርሱም ፡ ዝም ፡ አሉ ÷ አንዳችም ፡ አልመለሱለትም ፤ ንጉሡ ፡ እንዳይመልሱለት ፡ አዝዞ ፡ ነበርና ። ፳፪ የቤቱ ፡ አዛዥ ፡ የኬልቅያስ ፡ ልጅ ፡ ኤልያቄም ፡ ጸሐፊውም ፡ ሳምናስ ፡ ታሪክ ፡ ጸሐፊም ፡ የአሳፍ ፡ ልጅ ፡ ዮአስ ፡ ልብሳቸውን ፡ ቀድደው ፡ ወደ ፡ ሕዝቅያስ ፡ መጡ ÷ የራፋስቂስንም ፡ ቃል ፡ ነገሩት ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፯ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ ንጉሡ ፡ ሕዝቅያስ ፡ ይህን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ልብሱን ፡ ቀደደ ÷ ማቅም ፡ ለበሰ ÷ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ገባ ። ፪ የቤቱንም ፡ አዛዥ ፡ ኤልያቄምን ፡ ጸሐፊውንም ፡ ሳምናስን ፡ የካህናቱንም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ማቅ ፡ ለብሰው ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡ ወደ ፡ አሞጽ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢሳይያስ ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ላካቸው ። ፫ እነርሱም ፡— ሕዝቅያስ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ይህ ፡ ቀን ፡ የመከራና ፡ የተግሣጽ ፡ የዘለፋም ፡ ቀን ፡ ነው ፤ ልጆች ፡ የሚወለዱበት ፡ ጊዜ ፡ ደርሶአል ፡ ለመውለድም ፡ ኃይል ፡ የለም ። ፬ ምናልባት ፡ በሕያው ፡ አምላክ ፡ ላይ ፡ ይገዳደር ፡ ዘንድ ፡ ጌታው ፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ የላከውን ፡ የራፋስቂስን ፡ ቃል ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይሰማ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ አምላክህ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ስለ ፡ ሰማው ፡ ቃል ፡ ይገሥጸው ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ ስለዚህ ፡ ለቀረው ፡ ቅሬታ ፡ ጸልይ ፡ አሉት ።

፭ እንዲሁ ፡ የንጉሡ ፡ የሕዝቅያስ ፡ ባሪያዎች ፡ ወደ ፡ ኢሳይያስ ፡ መጡ ። ፮ ኢሳይያስም ፡— ለጌታችሁ ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ ባሪያዎች ፡ ስለ ፡ ሰደቡኝ ÷ ስለ ፡ ሰማኸው ፡ ቃል ፡ አትፍራ ። ፯ እነሆ ÷ በላዩ ፡ መንፈስን ፡ እሰድዳለሁ ÷ ወሬንም ፡ ይሰማል ÷ ወደ ፡ ምድሩም ፡ ይመለሳል ፤ በምድሩም ፡ በሰይፍ ፡ እንዲወድቅ ፡ አደርጋለሁ ፡ በሉት ፡ አላቸው ።

፰ የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ ከለኪሶ ፡ እንደ ፡ ራቀ ፡ ሰምቶ ፡ ነበርና ፡ ራፋስቂስ ፡ ተመልሶ ፡ በልብና ፡ ሲዋጋ ፡ አገኘው ። ፱ እርሱም ፡— የኢትዮጵያ ፡ ንጉሥ ፡ ቲርሐቅ ፡ ሊዋጋህ ፡ መጥቶአል ፡ የሚል ፡ ወሬ ፡ ሰማ ። በሰማም ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሕዝቅያስ ፡ መልእክተኞችን ፡ ላከ ÷ እንዲህ ፡ ሲል ፡— ፲ ለይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ለሕዝቅያስ ፡ እንዲህ ፡ ብላችሁ ፡ ንገሩት ፡— ኢየሩሳሌም ፡ በአሦር ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ አትሰጥም ፡ ብሎ ፡ የምትታመንበት ፡ አምላክህ ፡ አያታልልህ ። ፲፩ እነሆ ÷ የአሦር ፡ ነገሥታት ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያደረጉትን ÷ እንዴትስ ፡ እንዳጠፉአቸው ፡ ሰምተሃል ፤ አን

፲፪ ተስ ፡ ትድናለህን ? አባቶቼ ፡ ያጠፉአቸውን ፡ ጎዛንን ÷ ካራንን ÷ ራፌስን ÷ በተላሳር ፡ የነበሩትንም ፡ የዔድንን ፡ ልጆች ፡ የአሕዛብ ፡ አማልክት ፡ አዳኑአቸውን ? ፲፫ የሐማት ፡ ንጉሥ ÷ የአርፋድ ፡ ንጉሥ ÷ የሴፈርዋይም ፡ከተማ ፡ ንጉሥ ÷ የሄናና ፡ የዒዋ ፡ ንጉሥ ፡ ወዴት ፡ አሉ ?

፲፬ ሕዝቅያስም ፡ ደብዳቤውን ፡ ከመልእክተኞች ፡ እጅ ፡ ተቀብሎ ፡ አነበበው ፤ ሕዝቅያስም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ወጥቶ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ዘረጋው ። ፲፭ ሕዝቅያስም ፡ ወደ ፡ ፲፮ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ጸለየ ፡— አቤቱ ÷ በኪሩቤል ፡ ላይ ፡ የምትቀመጥ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ሆይ ÷ አንተ ፡ ብቻህን ፡ የምድር ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ አምላክ ፡ ነህ ፤ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ ፈጥረሃል ። ፲፯ አቤቱ ÷ ጆሮህን ፡ አዘንብልና ፡ ስማ ፤ አቤቱ ÷ ዓይንህን ፡ ክፈትና ፡ እይ ፤ በሕያው ፡ አምላክ ፡ ላይ ፡ ይገዳደር ፡ ዘንድ ፡ የላከውን ፡ የሰናክሬምን ፡ ቃል ፡ ስማ ። ፲፰ አቤቱ ÷ በእውነት ፡ የአሦር ፡ ነገሥታት ፡ ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ አገሮቻቸውንም ፡ አፍርሰዋል ÷ ፲፱ አማልክቶቻቸውንም ፡ በእሳት ፡ ላይ ፡ ጥለዋል ፤ የእንጨትና ፡ የድንጋይ ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ ሥራ ፡ ነበሩ ፡ እንጂ ፡ አማልክት ፡ አልነበሩም ፤ ፳ ምና ፡ ስለዚህ ፡ አጥፍተዋቸዋል ። እንግዲህም ፡ አምላካችን ፡ አቤቱ ÷ የምድር ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ ከእጁ ፡ አድነን ።

፳፩ የአሞጽ ፡ ልጅ ፡ ኢሳይያስ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ሕዝቅያስ ፡ ላከ ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ስለ ፡ አሦር ፡ ንጉሥ ፡ ስለ ፡ ሰናክሬም ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ለምነሃልና ፡ ፳፪ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ የተናገረው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ፡— ድንግሊቱ ፡ የጽዮን ፡ ልጅ ፡ ቀላል ፡ አድርጋሃለች ÷ በንቀትም ፡ ስቃብሃለች ፤ የኢየሩሳሌም ፡ ልጅ ፡ ራስዋን ፡ ነቅንቃብሃለች ። ፳፫ የተገዳደርኸው ፡ የሰደብኸውስ ፡ ማን ፡ ነው ? ቃልህንስ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደረግህበት ፡ ዓይንህንስ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ያነሣህበት ፡ ማን ፡ ነው ? በእስራኤል ፡ ቅዱስ ፡ ላይ ፡ ነው ። ፳፬ አንተም ፡— በሰረገላዬ ፡ ብዛት ፡ ወደ ፡ ተራሮች ፡ ከፍታ ÷ ወደ ፡ ሊባኖስ ፡ ጥግ ፡ ላይ ፡ ወጥቻለሁ ፤ ረጃጅሞቹንም ፡ ዝግባዎች ፡ የተመረጡትንም ፡ ጥዶች ፡ እቈርጣለሁ ÷ ወደ ፡ ከፍታውም ፡ ዳርቻ ፡ ወደ ፡ ቀርሜሎስ ፡ ዱር ፡ እገባለሁ ። ፳፭ ቈፈርሁም ፡ ውኃም ፡ ጠጣሁ ፡ የግብጽንም ፡ ወንዞች ፡ ሁሉ ፡ በእግሬ ፡ ጫማ ፡ አደርቃለሁ ፡ ብለህ ፡ በባሪያዎችህ ፡ እጅ ፡ በጌታ ፡ ላይ ፡ ተገዳደርህ ።

፳፮ እኔ ፡ ጥንቱን ፡ እንደ ፡ ሠራሁት ÷ ቀድሞውንም ፡ እንዳደረግሁት ፡ አልሰማህምን ? አሁንም ፡ የተመሸጉትን ፡ ከተሞች ፡ የፍርስራሽ ፡ ክምር ፡ እስኪሆኑ ፡ ድረስ ፡ እንድታፈርስ ፡ አደረግሁህ ። ፳፯ ስለዚህ ፡ የሚኖሩባቸው ፡ ሰዎች ፡ እጃቸው ፡ ዝሎአል ÷ ደንግጠውም ፡ ታውከዋል ፤ እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሣር ÷ እንደ ፡ ለመለመም ፡ ቡቃያ ÷ በሰገነትም ፡ ላይ ፡ እንዳለ ፡ ሣር ÷ ሳይሸት ፡ ዋግ ፡ እንደ ፡ መታውም ፡ እህል ፡ ሆነዋል ። ፳፰ እኔ ፡ ግን ፡ መቀመጫህንና ፡ መውጫህን ፡ መግቢያህንም ፡ በእኔም ፡ ላይ ፡ የተቈጣኸውን ፡ ቍጣ ፡ አውቄአለሁ ። ፳፱ ቍጣህና ፡ ትዕቢትህ ፡ ወደ ፡ ጆሮዬ ፡ ደርሶአልና ፡ ስለዚህ ፡ ስናጋዬን ፡ በአፍንጫህ ፡ ልጓሜንም ፡ በከንፈርህ ፡ አደርጋለሁ ÷ በመጣህበትም ፡ መንገድ ፡ እመልስሃለሁ ።

፴ ይህም ፡ ምልክት ፡ ይሆንሃል ፤ በዚህ ፡ ዓመት ፡ የገቦውን ÷ በሁለተኛውም ፡ ዓመት ፡ ከገቦው ፡ የበቀለውን ፡ ትበላላችሁ ፤ በሦስተኛውም ፡ ዓመት ፡ ትዘራላችሁ ፡ ታጭዱማላችሁ ÷ ወይንንም ፡ ትተክላላችሁ ፡ ፍሬውንም ፡ ትበላላችሁ ። ፴፩ ያመለጠው ፡ የይሁዳ ፡ ቤት ፡ ቅሬታ ፡ ሥሩን ፡ ወደ ፡ ታች ፡ ይሰድዳል ÷ ወደ ፡ ላይም ፡ ያፈራል ። ፴፪ ከኢየሩሳሌም ፡ ቅሬታ ፡ ከጽዮንም ፡ ተራራ ፡ ያመለጡት ፡ ይወጣሉና ፤ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቅንዓት ፡ ይህን ፡ ያደርጋል ። ፴፫ ስለዚህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ አሦር ፡ ንጉሥ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ወደዚች ፡ ከተማ ፡ አይመጣም ÷ ፍላጻንም ፡ አይወረውርባትም ÷ በጋሻም ፡ አይመጣባትም ÷ የአፈርንም ፡ ድልድል ፡ አይደለድልባትም ። ፴፬ በመጣበት ፡ መንገድ ፡ በዚያው ፡ ይመለሳል ÷ ወደዚችም ፡ ከተማ ፡ አይመጣም ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፴፭ ስለ ፡ እኔም ፡ ስለ ፡ ባሪያዬም ፡ ስለ ፡ ዳዊት ፡ ይህችን ፡ ከተማ ፡ አድናት ፡ ዘንድ ፡ እጋርዳታለሁ ።

፴፮ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ወጣ ÷ ከአሦራውያንም ፡ ሰፈር ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ገደለ ፤ ማለዳም ፡ በተነሡ ፡ ጊዜ ÷ እነሆ ÷ ሁሉ ፡ በድኖች ፡ ነበሩ ። ፴፯ የአሦርም ፡ ንጉሥ ፡ ሰናክሬም ፡ ተነሥቶ ፡ ሄደ ÷ ተመልሶም ፡ በነነዌ ፡ ተቀመጠ ። ፴፰ በአምላኩም ፡ በናሳራክ ፡ ቤት ፡ ሲሰግድ ፡ ልጆቹ ፡ አድራሜሌክና ፡ ሳራሳር ፡ በሰይፍ ፡ ገደሉት ፤ ወደ ፡ አራራትም ፡ አገር ፡ ኰበለሉ ። ልጁም ፡ አስራዶን ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፰ ።

፩ በዚያም ፡ ወራት ፡ ሕዝቅያስ ፡ ለሞት ፡ እስኪደርስ ፡ ታመመ ። ነቢዩም ፡ የአሞጽ ፡ ልጅ ፡ ኢሳይያስ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጥቶ ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ትሞታለህ ፡ እንጂ ፡ በሕይወት ፡ አትኖርምና ፡ ቤትህን ፡ አስተካክል ፡ አለው ። ፪ ሕዝቅያስም ፡ ፊቱን ፡ ወደ ፡ ግድግዳው ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸለየ ፡— ፫ አቤቱ ÷ በፊትህ ፡ በእውነትና ፡ በፍጹም ፡ ልብ ፡ እንደ ፡ ሄድሁ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝህንም ፡ እንዳደረግሁ ፡ ታስብ ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ። ሕዝቅያስም ፡ እጅግ ፡ አድርጎ ፡ አለቀሰ ። ፬ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ኢሳይያስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ፭ ሂድ ÷ ሕዝቅያስን ፡

እንዲህ ፡ በለው ፡— የአበትህ ፡ የዳዊት ፡ አም
ላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ጸሎ
ትህን ፡ ሰምቻለሁ ÷ እንባህንም ፡ አይቻለሁ ፤
እነሆ ÷ በዕድሜህ ፡ ላይ ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡
፮ ዓመት ፡ እጨምራለሁ ። አንተንና ፡ ይህችንም ፡
ከተማ ፡ ከአሦር ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ እታደጋለሁ ÷
፯ ይህችንም ፡ ከተማ ፡ እጋርዳታለሁ ። እግዚ
አብሔርም ፡ የተናገረውን ፡ ነገር ፡ እንዲፈጽ
መው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ምልክቱ ፡ ይህ ፡
፰ ይሆንልሃል ። እነሆ ÷ በአካዝ ፡ የጥላ ፡ ስፍረ ፡
ሰዓት ፡ ላይ ፡ ከፀሐይ ፡ ጋር ፡ የወረደውን ፡ በደ
ረጃዎች ፡ ያለውን ፡ ጥላ ፡ አሥር ፡ ደረጃ ፡ ወደ ፡
ኋላ ፡ እንዲመለስ ፡ አደርጋለሁ ። ፀሐይም ፡
በጥላ ፡ ስፍረ ፡ ሰዓት ፡ ላይ ፡ የወረደበት ፡ አሥር ፡
ደረጃ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ተመለሰ ።

፱ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ሕዝቅያስ ፡ ታምሞ ፡ ከደ
ዌው ፡ በተፈወሰ ፡ ጊዜ ፡ የጻፈው ፡ ጽሕፈት ፡
ይህ ፡ ነው ፡—

፲ እኔ ፡— በሕይወት ፡ ዘመኔ ፡ መካከል ፡ ወደ ፡
ሲኦል ፡ በሮች ፡ እገባለሁ ፤
የቀረው ፡ ዘመኔ ፡ ጐደለብኝ ፡ አልሁ ።
፲፩ ደግሞም ፡— በሕያዋን ፡ ምድር ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ አላይም ፤
በዓለምም ፡ ከሚኖሩ ፡ ጋር ፡ ሰውን ፡ እን
ግዲህ ፡ አልመለከትም ፡ አልሁ ።
፲፪ ማደሪያዬ ፡ ተነቀለች ÷
እንደ ፡ እረኛ ፡ ድንኳንም ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡
ተወገደች ፤
ሕይወቴንም ፡ እንደ ፡ ሸማኔ ፡ ጠቀለልሁ ÷
እርሱም ፡ ከመጠቅለያው ፡ ይቈርጠኛል ፤
ከማለዳ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡
ታጠፋኛለህ ።
፲፫ እስኪነጋ ፡ ድረስ ፡ ቈይቼ ፡ ነበር ፤
እርሱ ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ አጥንቴን ፡ ሁሉ ፡
ሰበረ ፤
ከማለዳ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡
ታጠፋኛለህ ።
፲፬ እንደ ፡ ጨረባና ፡ እንደ ፡ ሽመላ ፡ ተንጫ
ጫሁ ÷
እንደ ፡ ርግብም ፡ አጕረመረምሁ ፤
ዓይኖቼ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ከማየት ፡ ደከሙ ።
ጌታ ፡ ሆይ ÷ ተጨንቄአለሁና ፡ መከታ ፡
ሁነኝ ።
፲፭ ምን ፡ እላለሁ ? እርሱ ፡ ተናግሮኛል ÷
እርሱ ፡ ራሱም ፡ ይህን ፡ አድርጎአል ፤
በዘመኔ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ነፍሴ ፡ ምሬት ፡ ቀስ ፡
ብዬ ፡ እሄዳለሁ ።
፲፮ ጌታ ፡ ሆይ ÷ በዚህ ፡ ነገር ፡ ሰዎች ፡ በሕይ
ወት ፡ ይኖራሉ ÷
በዚህም ፡ ሁሉ ፡ የመንፈሴ ፡ ሕይወት ፡ ነው ፤
አንተም ፡ ፈወስኸኝ ፡ ወደ ፡ ሕይወትም ፡
መለስኸኝ ።
፲፯ እነሆ ÷ ታላቅ ፡ ምሬት ፡ ለደኅንነቴ ፡ ሆነ ፤
አንተም ፡ ነፍሴን ፡ ከጥፋት ፡ ጕድጓድ ፡ አዳ
ንሃት ÷
ኃጢአቴንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ኋላህ ፡ ጣልህ ።
፲፰ ሲኦል ፡ አያመሰግንህምና ÷ ሞትም ፡ አያ
ከብርህምና ፤
ወደ ፡ ጕድጓዱ ፡ የሚወርዱ ፡ እውነትህን ፡
ተስፋ ፡ አያደርጉም ።
፲፱ እኔ ፡ ዛሬ ፡ እንደማደርግ ፡ ሕያዋን ፡ እነ
ርሱ ፡ ያመሰግኑሃል ፤
አበት ፡ ለልጆች ፡ እውነትህን ፡ ያስታው
ቃል ።
፳ እግዚአብሔር ፡ ያድነኛል ፤
ስለዚህ ፡ በዕድሜያችን ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
ቅኔዎችን ፡ አውታር ፡ ባለው ፡ ዕቃ ፡ እንዘ
ምራለን ።

፳፩ ኢሳይያስም ፡— የበለስ ፡ ጥፍጥፍ ፡ አምጥ
ተው ፡ በእባጩ ፡ ላይ ፡ ይለብጡት ÷ እርሱም ፡
፳፪ ይፈወሳል ፡ ብሎ ፡ ነበር ። ሕዝቅያስም ፡— ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እወጣ ፡ ዘንድ ፡ ምልክቱ ፡
ምንድር ፡ ነው ? ብሎ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፱ ።

፩ በዚያም ፡ ወራት ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ የባል
ዳን ፡ ልጅ ፡ መሮዳክ ፡ ባልዳን ፡ ሕዝቅያስ ፡ ታምሞ ፡
እንደ ፡ ተፈወሰ ፡ ሰምቶ ፡ ነበርና ፡ ደብዳቤና ፡
፪ እጅ ፡ መንሻ ፡ ላከለት ። ሕዝቅያስም ፡ ደስ ፡
አለው ÷ ግምጃ ፡ ቤቱንም ÷ ብሩንና ፡ ወርቁ
ንም ÷ ቅመሙንና ፡ የከበረውንም ፡ ዘይት ÷ መሣ
ርያም ፡ ያለበትን ፡ ቤት ፡ ሁሉ ÷ በቤተ ፡ መዛግ
ብቱም ፡ የተገኘውን ፡ ሁሉ ፡ አሳያቸው ፤ በቤ
ቱና ፡ በግዛቱ ፡ ሁሉ ፡ ካለው ፡ ሕዝቅያስ ፡
፫ ያላሳያቸው ፡ የለም ። ነቢዩም ፡ ኢሳይያስ ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ሕዝቅያስ ፡ መጥቶ ፡— እነዚህ ፡
ሰዎች ፡ ምን ፡ አሉ ? ከወዴትስ ፡ መጡልህ ?
አለው ። ሕዝቅያስም ፡— ከሩቅ ፡ አገር ፡ ከባ
፬ ቢሎን ፡ መጡልኝ ፡ አለው ። እርሱም ፡— በቤ
ትህ ፡ ያዩት ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለው ፤ ሕዝ
ቅያስም ፡— በቤቴ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ አይተ
ዋል ፤ በቤተ ፡ መዛግብቴ ፡ ካለው ፡ ያላሳየኋ
፭ ቸው ፡ የለም ፡ አለው ። ኢሳይያስም ፡ ሕዝቅያ
ስን ፡— የሠራዊትን ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔርን ፡
፮ ቃል ፡ ስማ ። እነሆ ÷ በቤትህ ፡ ያለው ፡ ሁሉ ÷
አባቶችህም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ያከማቹት ፡
ሁሉ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ የሚፈልስበት ፡ ወራት ፡
ይመጣል ፤ ምንም ፡ አይቀርም ÷ ይላል ፡ እግዚ
፯ አብሔር ። ከአንተም ፡ ከሚወጡት ፡ ከምትወ
ልዳቸው ፡ ልጆችህ ፡ ማርከው ፡ ይወስዳሉ ፤
በባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ጃንደረ
፰ ቦች ፡ ይሆናሉ ፡ አለው ። ሕዝቅያስም ፡ ኢሳይያ
ስን ፡— የተናገርኸው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡
መልካም ፡ ነው ፡ አለው ። ደግሞም ፡— በዘ
መኔ ፡ ሰላምና ፡ እውነት ፡ ይሁን ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵ ።

፩ አጽናኑ ÷ ሕዝቤን ፡ አጽናኑ ፡ ይላል ፡ አምላ
፪ ካችሁ ። ለኢየሩሳሌም ፡ ልብ ፡ ተናገሩ ፤ የተቀ
ጠረችበት ፡ ወራት ፡ እንደ ፡ ተፈጸመ ÷ ኃጢአ
ትዋም ፡ እንደ ፡ ተሰረየ ÷ ከእግዚአብሔርም ፡
እጅ ፡ ስለ ፡ ኃጢአትዋ ፡ ሁሉ ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡
እንደ ፡ ተቀበለች ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ጩኹ ።
፫ የአዋጅ ፡ ነጋሪ ፡ ቃል ፡— የእግዚአብሔርን ፡
መንገድ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ጥረጉ ÷ ለአምላካች
፬ ንም ፡ ጐዳና ፡ በበረሀ ፡ አስተካክሉ ። ሸለቆው ፡
ሁሉ ፡ ከፍ ፡ ይላል ÷ ተራራውና ፡ ኮረብታውም ፡
ሁሉ ፡ ዝቅ ፡ ይላል ፤ ጠማማውም ፡ ይቃናል ÷
፭ ስርጓጕጡም ፡ ሜዳ ፡ ይሆናል ፤ የእግዚአብሔ
ርም ፡ ክብር ፡ ይገለጣል ÷ ሥጋ ፡ ለባሹም ፡ ሁሉ ፡
በአንድነት ፡ ያየዋል ÷ የእግዚአብሔር ፡ አፍ ፡
ይህን ፡ ተናግሮአልና ።
፮ ጩኽ ፡ የሚል ፡ ሰው ፡ ቃል ፤ ምን ፡ ብዬ ፡
ልጩኽ ? አልሁ ። ሥጋ ፡ ለባሽ ፡ ሁሉ ፡ ሣር ፡
ነው ÷ ክብሩም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
፯ አበባ ፡ ነው ። የእግዚአብሔር ፡ እስትንፋስ ፡
ይነፍስበታልና ፡ ሣሩ ፡ ይደርቃል ፡ አበባውም ፡
ይረግፋል ፤ በእውነት ፡ ሕዝቡ ፡ ሣር ፡ ነው ።
፰ ሣሩ ፡ ይደርቃል ፡ አበባውም ፡ ይረግፋል ÷
የአምላካችን ፡ ቃል ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ጸንታ ፡
ትኖራለች ።
፱ የምስራች ፡ የምትነግሪ ፡ ጽዮን ፡ ሆይ ÷ ከፍ ፡
ወዳለው ፡ ተራራ ፡ ውጪ ፤ የምስራች ፡ የምት
ነግሪ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ÷ ድምፅሽን ፡ በኃይል ፡
አንሺ ፤ አንሺ ÷ አትፍሪ ፤ ለይሁዳም ፡ ከተ
ሞች ፡— እነሆ ÷ አምላካችሁ ! ብለሽ ፡ ንገሪ ።
፲ እነሆ ÷ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ኃያል ፡
ይመጣል ፡ ክንዱም ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ይገዛል ፤
እነሆ ÷ ዋጋው ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ደመወዙም ፡
፲፩ በፊቱ ፡ ነው ። መንጋውን ፡ እንደ ፡ እረኛ ፡ ያሰ
ማራል ÷ ጠቦቶቹን ፡ በክንዱ ፡ ሰብስቦ ፡ በብ
ብቱ ፡ ይሸከማል ÷ የሚያጠቡትንም ፡ በቀስታ ፡
ይመራል ።
፲፪ ውኆችን ፡ በእፍኙ ፡ የሰፈረ ÷ ሰማይንም ፡
በስንዝር ፡ የለካ ÷ የምድርንም ፡ አፈር ፡ በመ
ስፈርያ ፡ ሰብስቦ ፡ የያዘ ÷ ተራሮችን ፡ በሚዛን ፡
ኮረብቶችንም ፡ በሚዛኖች ፡ የመዘነ ፡ ማን ፡
፲፫ ነው ? የእግዚአብሔርን ፡ መንፈስ ፡ ያዘዘ ÷
ወይስ ፡ አማካሪ ፡ ሆኖ ፡ ያስተማረው ፡ ማን ፡
፲፬ ነው ? ወይስ ፡ ከማን ፡ ጋር ፡ ተመካከረ ? ወይስ ፡
ማን ፡ መከረው ? የፍርድንም ፡ መንገድ ፡ ማን ፡
አስተማረው ? እውቀትንስ ፡ ማን ፡ አስተማ
ረው ? የማስተዋልንስ ፡ መንገድ ፡ ማን ፡ አሳ
፲፭ የው ? እነሆ ÷ አሕዛብ ፡ በገንቦ ፡ እንዳለች ፡
ጠብታ ፡ ናቸው ÷ በሚዛንም ፡ እንዳለ ፡ ትንሽ ፡
ትቢያ ፡ ተቈጥረዋል ፤ እነሆ ÷ ደሴቶችን ፡ እንደ ፡
፲፮ ቀላል ፡ ነገር ፡ ያነሣል ። ሊባኖስ ፡ ለማንደጃ ፡
እንስሶቹዋም ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ አይ
፲፯ በቁም ። አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ እንዳልነበሩ ፡
ናቸው ፤ ከምናምን ፡ እንደሚያንሱ ÷ እንደ ፡
ከንቱ ፡ ነገርም ፡ ይቈጥራቸዋል ።
፲፰ እንግዲህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በማን ፡ ትመስ
ሉታላችሁ ? ወይስ ፡ በምን ፡ ምሳሌ ፡ ታስተያ
፲፱ ዩታላችሁ ? የተቀረጸውንስ ፡ ምስል ፡ ሠራ
ተኛ ፡ ሠርቶታል ÷ አንጥረኛም ፡ በወርቅ ፡ ለብ
ጦታል ÷ የብሩንም ፡ ሰንሰለት ፡ አፍስሶለታል ።
፳ ለዚህ ፡ መባዕ ፡ ገንዘቡ ፡ ያልበቃው ፡ ድሀ ፡ የማ
ይነቅዘውን ፡ እንጨት ፡ ይመርጣል ፤ ምስሉም ፡
እንዳይናወጥ ፡ ያቆመው ፡ ዘንድ ፡ ብልሀ ፡ ሠራ
፳፩ ተኛን ፡ ይፈልጋል ። አላወቃችሁምን ? ወይስ ፡
አልሰማችሁምን ? ከጥንትስ ፡ አልተወራላች
ሁምን ? ወይስ ፡ ምድር ፡ ከተመሠረተች ፡ ጀምሮ ፡
፳፪ አላስተዋላችሁምን ? እርሱ ፡ በምድር ፡ ክበብ ፡
ላይ ፡ ይቀመጣል ÷ በእርስዋም ፡ የሚኖሩት ፡
እንደ ፡ አንበጣ ፡ ናቸው ፤ ሰማያትን ፡ እንደ ፡
መጋረጃ ፡ የሚዘረጋቸው ፡ እንደ ፡ ድንኳንም ፡
፳፫ ለመኖርያ ፡ የሚዘረጋቸው ÷ አለቆችንም ፡ እን
ዳልነበሩ ÷ የምድርንም ፡ ፈራጆች ፡ እንደ ፡
፳፬ ከንቱ ፡ ነገር ፡ የሚያደርጋቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።
ገና ፡ እንደ ፡ ተተከሉና ፡ እንደ ፡ ተዘሩ ÷ በምድ
ርም ፡ ሥር ፡ ገና ፡ እንደ ፡ ሰደዱ ፡ ወዲያውኑ ፡ ነፈ
ሰባቸው ÷ እነርሱም ፡ ደረቁ ÷ ዐውሎ ፡ ነፋስም ፡
፳፭ እንደ ፡ እብቅ ፡ ጠረጋቸው ። እንግዲህ ፡ እተ
ካከለው ፡ ዘንድ ፡ በማን ፡ መሰላችሁኝ ? ይላል ፡
፳፮ ቅዱሱ ። ዓይናችሁን ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ አንሥታችሁ ፡
ተመልከቱ ፤ እነዚህን ፡ የፈጠረ ፡ ማን ፡ ነው ?
ሠራዊታቸውን ፡ በቍጥር ፡ የሚያወጣ ፡ እርሱ ፡
ነው ÷ ሁሉንም ፡ በየስማቸው ፡ ይጠራቸዋል ፤
በኃይሉ ፡ ብዛትና ፡ በችሎቱ ፡ ብርታት ፡ አን
ድስ ፡ እንኳ ፡ አይታጣውም ።
፳፯ ያዕቆብ ፡ ሆይ ÷ እስራኤልም ፡ ሆይ ፡— መን
ገዴ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ተሰውራለች ፡ ፍርዴም ፡
ከአምላኬ ፡ አልፋለች ፡ ለምን ፡ ትላለህ ? ለም
፳፰ ንስ ፡ እንዲህ ፡ ትናገራለህ ? አላወቅህምን ?
አልሰማህምን ? እግዚአብሔር ፡ የዘላለም ፡ አም
ላክ ÷ የምድርም ፡ ዳርቻ ፡ ፈጣሪ ፡ ነው ፤ አይደ
ክምም ÷ አይታክትም ÷ ማስተዋሉም ፡ አይ
፳፱ መረመርም ። ለደካማ ፡ ኃይልን ፡ ይሰጣል ÷
ጕልበት ፡ ለሌለውም ፡ ብርታትን ፡ ይጨም
፴ ራል ። ብላቴኖች ፡ ይደክማሉ ፡ ይታክቱማል ÷
፴፩ ጐበዛዝቱም ፡ ፈጽሞ ፡ ይወድቃሉ ፤ እግዚአ
ብሔርን ፡ በመተማመን ፡ የሚጠባበቁ ፡ ግን ፡
ኃይላቸውን ፡ ያድሳሉ ፤ እንደ ፡ ንስር ፡ በክንፍ ፡
ይወጣሉ ፤ ይሮጣሉ ÷ አይታክቱም ፤ ይሄዳሉ ÷
አይደክሙም ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፩ ።

፩ ደሴቶች ፡ ሆይ ÷ በፊቴ ፡ ዝም ፡ በሉ ፤ አሕዛ
ብም ፡ ኃይላቸውን ፡ ያድሱ ፤ ይቅረቡም ፡ በዚ
ያን ፡ ጊዜም ፡ ይናገሩ ፤ ለፍርድ ፡ በአንድነት ፡
፪ እንቅረብ ። ከምሥራቅ ፡ አንዱን ፡ ያስነሣ ፡ በጽ
ድቅም ፡ ወደ ፡ እግሩ ፡ የጠራው ፡ ማን ፡ ነው ?
አሕዛብንም ፡ አሳልፎ ፡ በፊቱ ፡ ሰጠው ÷ ነገሥ

ታትንም፡አስገዛለት፤ለሰይፉ፡እንደ፡ትቢያ፡
ለቀስቱም፡እንደ፡ተጠረገ፡እብቅ፡አድርጎ፡
፫፡ ሰጣቸው። አሳደዳቸው፥እግሮቹም፡አስቀድ
መው፡ባልሄዱበት፡መንገድ፡በደኅንነት፡
፬፡ አለፈ። ይህን፡የሠራና፡ያደረገ፥ትውልድ
ንም፡ከጥንት፡የጠራ፡ማን፡ነው? እኔ፡እግ
ዚአብሔር፥ፊተኛው፡በኋለኞችም፡ዘንድ፡
፭፡ የምኖር፥እኔ፡ነኝ። ደሴቶች፡አይተው፡ፈሩ፥
የምድርም፡ዳርቻች፡ተንቀጠቀጡ፤ቀረቡም፡
፮፡ ደረሱም። ሁሉም፡እያንዳንዱ፡ባልንጀራ
ውን፡ይረዳው፡ነበር፥ወንድሙንም፡— አይ
፯፡ ዞህ፡ይለው፡ነበር። አናጢውም፡አንጥረኛ
ውን፥በመዶሻም፡የሚያሳሳውን፡መስፍ
መችውን፡አጽናና፥ ስለ፡ማጣበቅ፡ሥራ
ውም፡— መልካም፡ነው፡አለ፤እንዳይንቀሳ
ቀስም፡በችንካር፡አጋጠመው።

፰፡ ባሪያዬ፡እስራኤል፥የመረጥሁህ፡ያዕቆብ፥
፱፡ የወዳጄ፡የአብርሃም፡ዘር፡ሆይ፥አንተ፡ከም
ድር፡ዳርቻ፡የያዝሁህ፡ከማዕዘንዋም፡የጠራ
ሁህና፡— አንተ፡ባሪያዬ፡ነህ፥መርጬሃለሁ፡
፲፡ አልጥልህም፡ያልሁህ፡ሆይ፥እኔ፡ከአንተ፡
ጋር፡ነኝና፡አትፍራ፤እኔ፡አምላክህ፡ነኝና፡
አትደንግጥ፤አበረታሃለሁ፥እረዳህማለሁ፥
፲፩፡ በጽድቄም፡ቀኝ፡ደግፌ፡እይዝሃለሁ። እነሆ፥
የሚቆጡህ፡ሁሉ፡ያፍራሉ፥ይዋረዱማል፤
የሚከራከሩህም፡እንዳልነበሩ፡ይሆናሉ፥ይጠ
፲፪፡ ፉማል። የሚያጣሉህንም፡ትሻቸዋለህ፡አታ
ገኛቸውምም፥የሚዋጉህም፡እንዳልነበሩና፡
፲፫፡ እንደ፡ምናምን፡ይሆናሉ። እኔ፡አምላክህ፡
እግዚአብሔር፡— አትፍራ፥እረዳሃለሁ፡ብዬ፡
፲፬፡ ቀኝህን፡እይዛለሁና። አንተ፡ትል፡ያዕቆብ፡
የእስራኤልም፡ሰዎች፡ሆይ፥አትፍሩ፤እረዳ
ሃለሁ፥ይላል፡እግዚአብሔር፥የሚቤዥህም፡
፲፭፡ የእስራኤል፡ቅዱስ፡ነው። እነሆ፥እንደ፡ተሳ
ለች፡እንደ፡አዲስ፡ባለ፡ጥርስ፡ማሄጃ፡አድ
ርጌሃለሁ፤ተራሮችንም፡ታሄዳለህ፡ታደቅቃ
ቸውማለህ፥ኮረብቶችንም፡እንደ፡ገለባ፡ታደ
፲፮፡ ርጋቸዋለህ። ታበጥራቸዋለህ፥ነፋስም፡ይጠ
ርጋቸዋል፥ዐውሎ፡ነፋስም፡ይበትናቸዋል፤
አንተም፡በእግዚአብሔር፡ደስ፡ይልሃል፥በእ
ስራኤልም፡ቅዱስ፡ትመካለህ።

፲፯፡ ድሆችና፡ምስኪኖችም፡ውኃ፡ይሻሉ፡አያ
ገኙምም፥ምላሳቸውም፡በጥማት፡ደርቋል፤
እኔ፡እግዚአብሔር፡እሰማቸዋለሁ፥የእስራ
፲፰፡ ኤል፡አምላክ፡እኔ፡አልተዋቸውም። በወና
ምቹ፡ኮረብቶች፡ላይ፡ወንዞችን፥በሸለቆችም፡
መካከል፡ምንጮችን፡እከፍታለሁ፤ምድረ፡
በዳውን፡ለውኃ፡መቆሚያ፥የጥማትንም፡
ምድር፡ለውኃ፡መፍለቂያ፡አደርጋለሁ።
፲፱፡፳፡ የእግዚአብሔር፡እጅ፡ይህን፡እንደ፡ሠራች፥
የእስራኤልም፡ቅዱስ፡እንደ፡ፈጠረው፡ያዩ፡
ዘንድ፡ያውቁም፡ዘንድ፡ያስቡም፡ዘንድ፡በአ
ንድነትም፡ያስተውሉ፡ዘንድ፥በምድረ፡በዳ፡
ዝግባውንና፡ግራሩን፡ባርሰነቱንና፡የዘይቱን፡
ዛፍ፡አበቅላለሁ፥በበረሀውም፡ጥዱንና፡አስ
ታውን፡ወይራውንም፡በአንድነት፡አኖራለሁ።

፳፩፡ ክርክራችሁን፡አቅርቡ፥ይላል፡እግዚአ
ብሔር፤ማስረጃችሁን፡አምጡ፥ይላል፡
፳፪፡ የያዕቆብ፡ንጉሥ። ያምጡ፥የሚሆነውንም፡
ይንገሩን፤ልብም፡እናደርግ፡ዘንድ፡ፍጻሜአ
ቸውንም፡እናውቅ፡ዘንድ፥የቀደሙት፡ነገ
ሮች፡ምን፡እንደ፡ሆኑ፡ተናገሩ፥የሚመጡ
፳፫፡ ትንም፡አሳዩን። አማልክትም፡መሆናችሁን፡
እናውቅ፡ዘንድ፡በኋላ፡የሚመጡትን፡ተና
ገሩ፤እንደነግጥም፡ዘንድ፡በአንድነትም፡
እናይ፡ዘንድ፡መልካሙን፡ወይም፡ክፉውን፡
፳፬፡ አድርጉ። እነሆ፥እንዳልነበረ፡ናችሁ፥ሥራ
ችሁም፡ከንቱ፡ነው፤የሚመርጣችሁም፡አስ
ጸያፊ፡ነው።

፳፭፡ አንዱን፡ከሰሜን፡አነሣሁ፡መጥቶአልም፤
አንዱም፡ከፀሐይ፡መውጫ፡ስሜን፡የሚጠራ፡
ይመጣል፤በጭቃ፡ላይ፡እንደሚመጣ፡ሰው፡
አፈርም፡እንደሚረግጥ፡ሸክላኛ፡በአለቆች፡
፳፮፡ ላይ፡ይመጣል። እናውቅ፡ዘንድ፡ከጥንት፡
የተናገረው፡— እውነት፡ነው፡እንልም፡ዘንድ፡
ቀድሞ፡የተናገረው፡ማን፡ነው? የሚናገር፡
የለም፥የሚገልጥም፡የለም፥ቃላችሁንም፡
፳፯፡ የሚሰማ፡የለም። በመጀመሪያ፡ለጽዮን፡— እነ
ኋቸው፡እላለሁ፤ለኢየሩሳሌምም፡የምስራች፡
፳፰፡ ነጋሪን፡እሰጣለሁ። ብመለከት፡ማንም፡አል
ነበረም፤ብጠይቃቸውም፡የሚመልስልኝ፡
፳፱፡ አማካሪ፡በመካከላቸው፡የለም። እነሆ፥እነ
ርሱ፡ሁሉ፡ከንቱዎች፡ናቸው፥ሥራቸውም፡
ምንምን፡ናት፤ቀልጠው፡የተሠሩት፡ምስ
ሎቻቸውም፡ነፋስና፡ኢምንት፡ናቸው።

## ምዕራፍ፡፵፪።

፩፡ እነሆ፡ደግፌ፡የያዝሁት፡ባሪያዬ፤ነፍሴ፡
ደስ፡የተሰኘችበት፡ምርጤ፤በእርሱ፡ላይ፡
መንፈሴን፡አድርጌአለሁ፥እርሱም፡ለአሕዛብ፡
፪፡ ፍርድን፡ያወጣል። አይጮኽም፡ቃሉንም፡
አያነሣም፥ድምፁንም፡በሜዳ፡አያሰማም።
፫፡ የተቀጠቀጠን፡ሸምበቆ፡አይሰብርም፥የሚ
ጤስንም፡ክር፡አያጠፋም፤በእውነት፡ፍር
፬፡ ድን፡ያወጣል። በምድርም፡ፍርድን፡እስኪ
ያደርግ፡ድረስ፡ይበራል፡እንጂ፡አይጠፋም፤
አሕዛብም፡በስሙ፡ይታመናሉ።

፭፡ ሰማያትን፡የፈጠረ፡የዘረጋቸውም፥ምድ
ርንና፡በውስጥዋ፡ያለውን፡ያጸና፥በእርስዋ፡
ላይ፡ለሚኖሩ፡ሕዝብ፡እስትንፋስን፥ለሚሄ
ዱብትም፡መንፈስን፡የሚሰጥ፡አምላክ፡እግዚ
፮፡፯፡ አብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— እኔ፡እግዚአብሔር፡
በጽድቅ፡ጠርቼሃለሁ፥እጅህንም፡እይዛለሁ፡
እጠብቅህማለሁ፥የዕውሩንም፡ዓይን፡ትከ
ፍት፡ዘንድ፡የተጋዘውንም፡ከግዞት፡ቤት፡
በጨለማም፡የተቀመጡትን፡ከወህኒ፡ቤት፡
ታወጣ፡ዘንድ፡ለሕዝብ፡ቃል፡ኪዳን፡ለአሕ
፰፡ ዛብም፡ብርሃን፡አድርጌ፡እሰጥሃለሁ። እኔ፡

እግዚአብሔር፡ነኝ፤ ስሜ፡ይህ፡ነው፤ ክብ ሬን፡ለሌላ፥ ምስጋናዬንም፡ለተቀረጹ፡ምስ ፱፤ ሎች፡አልሰጥም። እነሆ፥ የቀድሞው፡ነገር፡ ተፈጸመ፥ አዲስ፡ነገርንም፡እናገራለሁ፤ አስ ቀድሞም፡ ሳይበቅል፡እርሱን፡አስታውቃ ችኋለሁ።

፲፤ ወደ፡ባሕር፡የምትወርዱ፡በእርስዋም፡ ውስጥ፡ያላችሁ፡ሁሉ፥ ደሴቶችና፡በእነር ሱም፡ላይ፡የምትኖሩ፡ሆይ፥ለእግዚአብሔር፡ አዲስ፡መዝሙር፥ ከምድርም፡ዳርቻ፡ምስ ፲፩፤ ጋናውን፡ዘምሩ። ምድረ፡በዳውና፡ከተሞቹ፡ የቄዳርም፡ሰዎች፡የሚቀመጡባቸው፡መንደ ሮች፡ድምፃቸውን፡ያንሡ፤ በሴላ፡የሚኖሩ፡ እልል፡ይበሉ፥በተራሮችም፡ራስ፡ላይ፡ሆነው፡ ፲፪፤ ይጮኹ። ለእግዚአብሔር፡ክብርን፡ይስጡ፥ ፲፫፤ ምስጋናውንም፡በደሴቶች፡ይናገሩ። እግዚአ ብሔር፡እንደ፡ኃያል፡ይወጣል፡እንደ፡ሰልፈ ኛም፡ቅንዓትን፡ያስነሣል፤ ይጮኻል፡ድምፁ ንም፡ያሰማል፡በጠላቶቹም፡ላይ፡ይበረታል።

፲፬፤ ከድሮ፡ዘመን፡ጀምሮ፡ዝም፡ብያለሁ፥ ዝም፡ብዬም፡ታግሻለሁ፤ አሁን፡ምጥ፡እንደ፡ ያዛት፡ሴት፡እጮኻለሁ፤ አጠፋለሁ፡በአን ፲፭፤ ድነትም፡እጨርሳለሁ። ተራሮችንና፡ኮረ ብቶችን፡አፈርሳለሁ፥ ቡቃያዎቻቸውንም፡ ሁሉ፡አደርቃለሁ፤ ወንዞችንም፡ደሴቶች፡ አደርጋለሁ፥ ኵሬዎችንም፡አደርቃለሁ። ፲፮፤ ዕውሮችንም፡በማያውቋት፡መንገድ፡አመጣቸ ዋለሁ፥በማያውቋትም፡ጎዳና፡እመራቸዋለሁ፤ በፊታቸውም፡ጨለማውን፡ብርሃን፡አደርጋ ለሁ፥ ጠማማውንም፡አቀናለሁ። ይህን፡አደ ፲፯፤ ርግላቸዋለሁ፥ አልተዋቸውምም። በተቀረጹ ትም፡ምስሎች፡የሚታመኑ፥ቀልጠው፡የተ ሠሩትንም፡ምስሎች፡— አምላኮቻችን፡ናችሁ፡ የሚሉ፡ወደ፡ኋላቸው፡ይመለሳሉ፡ፈጽመ ውም፡ያፍራሉ።

፲፰፤ እናንተ፡ደንቆሮች፥ ስሙ፤ እናንተም፡ ፲፱፤ ዕውሮች፥ታዩ፡ዘንድ፡ተመልከቱ። ከባሪያዬ፡ በቀር፡ዕውር፡ማን፡ነው? እንደምል ከው፡መልእክተኛዬስ፡በቀር፡ደንቆሮ፡ የሆነ፡ማን፡ነው? እንደ፡ፍጹሙ፡ወይስ፡ እንደ፡እግዚአብሔር፡ባሪያ፡ዕውር፡የሆነ፡ ፳፤ ማን፡ነው? ብዙ፡ነገርን፡ታያላችሁ፡ነገር፡ ግን፡አትጠባበቁትም፤ ጆሮአችሁም፡ተከፍተ ፳፩፤ ዋል፥ነገር፡ግን፡አትሰሙም። እግዚአብሔር፡ ስለ፡ጽድቁ፡ሕጉን፡ታላቅ፡ያደርግና፡ያከብር፡ ፳፪፤ ዘንድ፡ወደደ። ይህ፡ግን፡የተበዘበዘና፡ የተዘረፈ፡ሕዝብ፡ነው፤ ሁላቸው፡በዋሻ፡ ውስጥ፡ተጠምደዋል፡በግዞት፡ቤትም፡ተሸ ሽገዋል፤ ብዝበዛ፡ሆነዋል፡የሚያድንም፡ የለም፥ምርኮም፡ሆነዋል፥ማንም፡— መልሱ፡ አይልም።

፳፫፤ ከመካከላችሁ፡ይህን፡የሚያደምጥ፥ለሚ መጣውም፡ጊዜ፡የሚያደምጥና፡የሚሰማ፡ ፳፬፤ ማን፡ነው? ያዕቆብን፡ለማረኩ፡እስራኤል ንም፡ለበዘበዙ፡ሰዎች፡የሰጠ፡ማን፡ነው? እኛ፡ የበደልነው፥ እነርሱም፡በመንገዱ፡ይሄዱ፡ ዘንድ፡ያልወደዱት፡ለሕጉም፡ያልታዘዙለት፡ እግዚአብሔር፡እርሱ፡አይደለምን? ስለዚህ፡ ፳፭፤ የቍጣውን፡መዓትና፡የሰልፉን፡ጽናት፡አፈ ሰሰበት፤ በዙሪያም፡አነደደው፡እርሱ፡ግን፡ አላወቀም፥ አቃጠለውም፡እርሱ፡ግን፡ልብ፡ አላደረገም።

ምዕራፍ፡፵፫።

፩፤ አሁንም፡ያዕቆብ፡ሆይ፥ የፈጠረህ፥ እስራ ኤልም፡ሆይ፥ የሠራህ፡እግዚአብሔር፡እን ዲህ፡ይላል፡— ተቤዥቼሃለሁና፡አትፍራ፤ በስምህም፡ጠርቼሃለሁ፥ አንተ፡የእኔ፡ነህ። ፪፤ በውኃ፡ውስጥ፡ባለፍህ፡ጊዜ፡ከአንተ፡ጋር፡ እሆናለሁ፥ በወንዞችም፡ውስጥ፡ባለፍህ፡ ጊዜ፡አያሰጥሙህም፤ በእሳትም፡ውስጥ፡በሄ ድህ፡ጊዜ፡አትቃጠልም፥ ነበልባሉም፡አይ ፫፤ ፈጅህም። እኔ፡የእስራኤል፡ቅዱስ፡አምላ ክህ፡እግዚአብሔር፡መድኃኒትህ፡ነኝ፤ ግብ ጽን፡ለአንተ፡ቤዛ፡አድርጌ፥ ኢትዮጵያንና፡ ፬፤ ሳባንም፡ለአንተ፡ፋንታ፡ሰጥቻለሁ። በዓይኔ፡ ፊት፡የከበርህና፡የተመሰገንህ፡ነህና፥ እኔም፡ ወድጄሃለሁና፡ስለዚህ፡ሰዎችን፡ለአንተ፡ ፭፤ አሕዛብንም፡ለነፍስህ፡እሰጣለሁ። እኔ፡ከአ ንተ፡ጋር፡ነኝና፡አትፍራ፤ ዘርህንም፡ከምሥ ራቅ፡አመጣዋለሁ፥ ከምዕራብም፡እሰበስብሃ ፮፤፯፤ ለሁ። ሰሜንን፡— መልስህ፡አምጣ፥ ደቡብ ንም፡— አትከልክል፤ ወንዶች፡ልጆቼን፡ከሩቅ፡ ሴቶች፡ልጆቼንም፡ከምድር፡ዳርቻ፥ በስሜ፡ የተጠራውን፡ለክብሬም፡የፈጠርሁትን፥ የሠ ራሁትንና፡ያደረግሁትን፡ሁሉ፡አምጣ፡እለ ዋለሁ።

፰፤ ዓይኖች፡ያሉአቸውን፡ዕውሮችን፡ሕዝብ፥ ጆሮችም፡ያሉአቸውን፡ደንቆሮቹን፡አውጣ። ፱፤ አሕዛብ፡ሁሉ፡በአንድነት፡ይሰብሰቡ፡ወገኖ ችም፡ይከማቹ፤ ከመካከላቸው፡ይህን፡የሚና ገር፥የቀድሞውንስ፡ነገር፡የሚያሳየን፡ማን፡ ነው? ይጸድቁ፡ዘንድ፡ምስክሮቻቸውን፡ ያምጡ፥ሰምተውም፡— እውነት፡ነው፡ይበሉ። ፲፤ ታውቁና፡ታምኑብኝ፡ዘንድ፡እኔም፡እንደ፡ ሆንሁ፡ታስተውሉ፡ዘንድ፥እናንተ፡የመረጥሁ ትም፡ባሪያዬ፡ምስክሮቼ፡ናችሁ፡ይላል፡እግ ዚአብሔር፤ ከእኔ፡በፊት፡አምላክ፡አልተሠ ፲፩፤ ራም፡ከእኔም፡በኋላ፡አይሆንም። እኔ፥ እኔ፡ እግዚአብሔር፡ነኝ፥ ከእኔ፡ሌላም፡የሚያድን፡ ፲፪፤ የለም። ተናግሬአለሁ፡አድኛለሁ፡አሳይቼ ማለሁ፥ በእናንተም፡ዘንድ፡ባዕድ፡አምላክ፡ አልነበረም፤ ስለዚህ፡እናንተ፡ምስክሮቼ፡ ናችሁ፥ ይላል፡እግዚአብሔር፥ እኔም፡አም ፲፫፤ ላክ፡ነኝ። ከጥንት፡ጀምሮ፡እኔ፡ነኝ፡ከእ ጄም፡የሚያመልጥ፡የለም፤ እሠራለሁ፥የሚ ከለክልስ፡ማን፡ነው?

፲፬፤ የእስራኤል፡ቅዱስ፥የሚቤዣችሁ፥እግዚ

አብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ስለ ፡ እናንተ ፡
ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ሰድጃለሁ ÷ ከለዳውያንንም ፡
ሁሉ ፡ ስደተኞች ፡ አድርጌ ፡ በሚመኩባቸው ፡
፲፭ መርከቦች ፡ አዋርዳቸዋለሁ ። ቅዱሳችሁ ÷ የእ
ስራኤል ፡ ፈጣሪ ÷ ንጉሣችሁ ÷ እግዚአብሔር ፡
፲፮ እኔ ፡ ነኝ ። እግዚአብሔር ፡ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ መን
ገድን ፡ በኃይለኛም ፡ ውኃ ፡ ውስጥ ፡ መተላለፊ
፲፯ ያን ፡ ያደርጋል ፤ እግዚአብሔር ፡ ሰረገላውንና ፡
ፈረሱን ፡ ሠራዊቱንና ፡ አርበኛውን ፡ ያወጣል ፤
እነርሱ ፡ ግን ፡ በአንድነት ፡ ተኝተዋል ÷ አይነ
ሡም ፤ ቀርተዋል ÷ እንደ ፡ ጥዋፍ ፡ ኩስታሪም ፡
ጠፍተዋል ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
፲፰ የፊተኛውን ፡ ነገር ፡ አታስተውሉ ÷ የጥንቱ
፲፱ ንም ፡ ነገር ፡ አታስቡ ። እነሆ ÷ አዲስ ፡ ነገርን ፡
አደርጋለሁ ፤ እርሱም ፡ አሁን ፡ ይበቅላል ÷
እናንተም ፡ አታውቁትምን ? በምድረ ፡ በዳም ፡
መንገድን ፡ በበረሀም ፡ ወንዞችን ፡ አደርጋለሁ ።
፳ ፡ ፳፩ ምስጋናዬን ፡ እንዲናገሩ ፡ ለእኔ ፡ የፈጠርሁት ፡
ሕዝብ ÷ የመረጥሁትን ፡ ሕዝቤን ፡ አጠጣ ፡
ዘንድ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ውኃን ፡ በበረሀም ፡ ወን
ዞችን ፡ ሰጥቻለሁና ፡ የምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊት ÷
ቀበሮችና ፡ ሰጎኖች ÷ ያከብሩኛል ።

፳፪ ያዕቆብ ፡ ሆይ ÷ አንተ ፡ ግን ፡ አልጠራኸ
ኝም ÷ አንተም ፡ እስራኤል ፡ ሆይ ÷ በእኔ ፡
፳፫ ዘንድ ፡ ደክመሃል ። ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡
በጎችህን ፡ አላቀረብህልኝም ፡ በሌላም ፡ መሥ
ዋዕትህ ፡ አላከበርኸኝም ፤ በእህልም ፡ ቍርባን ፡
አላስቸገርሁህም ፡ በዕጣንም ፡ አላደከምሁህም ።
፳፬ ዕጣንም ፡ በገንዘብ ፡ አልገዛህልኝም ፡ በመሥዋ
ዕትህም ፡ ስብ ፡ አላጠገብኸኝም ፤ ነገር ፡ ግን ፡
በኃጢአትህ ፡ አስቸገርኸኝ ÷ በበደልህም ፡ አደ
ከምኸኝ ።

፳፭ መተላለፍህን ፡— ስለ ፡ እኔ ፡ ስል ፡ የምደመ
ስስ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ ኃጢአትህንም ፡ አላስብም ።
፳፮ አሳስበኝ ÷ በአንድነትም ፡ ሆነን ፡ እንፋረድ ፤
፳፯ እንድትጸድቅ ፡ ነገርህን ፡ ተናገር ። ፊተኛው ፡
አባትህ ፡ ኃጢአት ፡ ሠርቶአል ÷ መምህሮች
፳፰ ህም ፡ በድለውኛል ። ስለዚህ ፡ የመቅደሱን ፡ አለ
ቆች ፡ አረክሳለሁ ÷ ያዕቆብንም ፡ እርግማን ÷ እስ
ራኤልንም ፡ ስድብ ፡ አደረግሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፬ ።

፩ አሁንም ፡ ባሪያዬ ፡ ያዕቆብ ፡ የመረጥሁህም ፡
፪ እስራኤል ፡ ሆይ ÷ ስማ ። የፈጠረህ ፡ ከማኅፀ
ንም ፡ የሠራህ ፡ የሚረዳህም ፡ እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— ባሪያዬ ፡ ያዕቆብ ፡ የመረጥ
፫ ሁህም ፡ ይሹሩን ፡ ሆይ ÷ አትፍራ ። በተጠማ ፡
ላይ ፡ ውኃን ፡ በደረቅም ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ፈሳሾ
ችን ፡ አፈስሳለሁና ፤ መንፈሴን ፡ በዘርህ ፡ ላይ ፡
፬ በረከቴንም ፡ በልጆችህ ፡ ላይ ፡ አፈስሳለሁ ÷ በፈ
ሳሾችም ፡ አጠገብ ፡ እንደሚበቅሉ ፡ እንደ ፡
አኻያ ፡ ዛፎች ፡ በሣር ፡ መካከል ፡ ይበቅላሉ ።
፭ ይህ ፡— እኔ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነኝ ፡ ይላል ÷
ያም ፡ በያዕቆብ ፡ ስም ፡ ይጠራል ፤ ይህም ፡— እኔ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ በእጁ ፡ ይጽፋል ፡
በእስራኤልም ፡ የቍልምጫ ፡ ስም ፡ ይጠራል ።

፮ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ እግዚአብሔር ÷ የሚ
ቤዠም ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፡— እኔ ፡ ፊተኛ ፡ ነኝ ፡ እኔም ፡ ኋለኛ ፡
፯ ነኝ ÷ ከእኔ ፡ ሌላም ፡ አምላክ ፡ የለም ። እንደ ፡
እኔ ፡ ያለ ፡ ማን ፡ ነው ? ይነሣና ፡ ይጥራ ፡ ይናገ
ርም ፤ ከጥንት ፡ የፈጠርሁትን ፡ ሕዝብ ፡ ያዘጋጅ
ልኝ ÷ የሚመጣውም ፡ ነገር ፡ ሳይደርስ ፡ ይን
፰ ገሩኝ ። አትፍሩ ፡ አትደንግጡም ፤ ከጥንቱ ፡
ጀምሬ ፡ አልነገርኋችሁምን ? ወይስ ፡ አላሳየኋ
ችሁምን ? እናንተ ፡ ምስክሮቼ ፡ ናችሁ ። ከእኔ ፡
ሌላ ፡ አምላክ ፡ አለን ? አምባ ፡ የለም ፤ ማንንም ፡
አላውቅም ።

፱ የተቀረጸውን ፡ ምስል ፡ የሚሠሩ ፡ ሁሉ ፡ ከን
ቱዎች ፡ ናቸው ÷ የወደዱትም ፡ ነገር ፡ አይረባ
ቸውም ፤ ምስክሮቻቸውም ፡ አያዩምና ፡ አያው
፲ ቁም ፤ ስለዚህ ፡ ያፍራሉ ። አምላክን ፡ የሠራ ፡
ወይስ ፡ ለምንም ፡ የማይረባ ፡ ምስልን ፡ የቀረጸ ፡
፲፩ ማን ፡ ነው ? እነሆ ÷ ባልንጀሮቹ ፡ ሁሉ ፡ ያፍ
ራሉ ÷ ሠራተኞቹም ፡ ከሰዎች ፡ ወገን ፡ ናቸው ፤
ሁላቸው ፡ ተሰብስበው ፡ ይቁሙ ፤ ይፈራሉ ፡
በአንድነትም ፡ ያፍራሉ ።

፲፪ ብረት ፡ ሠሪ ፡ መጥረቢያውን ፡ ይሠራል ÷
በፍምም ፡ ውስጥ ፡ ያደርገዋል ÷ በመዶሻም ፡
መትቶ ፡ ቅርጽ ፡ ይሰጠዋል ÷ በክንዱም ፡ ኃይል ፡
ይሠራዋል ÷ እርሱም ፡ ይራባል ፡ ይደክምማል ÷
፲፫ ውኃም ፡ አይጠጣም ፡ ይታክትማል ። ጠራቢ
ውም ፡ ገመድ ፡ ይዘረጋል ፡ በበረቅም ፡ ያመለ
ክተዋል ፡ በመቅረጫም ፡ ይቀርጸዋል ፡ በመለ
ኪያም ፡ ይለክዋል ፤ በቤትም ፡ ውስጥ ፡ ይቀ
መጥ ፡ ዘንድ ፡ በሰው ፡ አምሳልና ፡ በሰው ፡
፲፬ ውበት ፡ ያስመስለዋል ። የዝግባን ፡ ዛፎች ፡
ይቈርጣል ፤ የዘጲንና ፡ የኮምበልን ፡ ዛፍ ፡ ይመ
ርጣል ÷ ከዱር ፡ ዛፎችም ፡ መካከል ፡ ይጠነክር ፡
ዘንድ ፡ ይተወዋል ፤ የጥድንም ፤ ዛፍ ፡ ይተክ
፲፭ ላል ፡ ዝናብም ፡ ያበቅለዋል ። ለሰውም ፡ ማገዶ ፡
ይሆናል ፤ ከእርሱም ፡ ወስዶ ፡ ይሞቃል ÷ አን
ድዶም ፡ እንጀራ ፡ ይጋግርበታል ፤ ከእርሱም ፡
አምላክ ፡ አበጅቶ ፡ ይሰግድለታል ÷ የተቀረጸ
ውንም ፡ ምስል ፡ ሠርቶ ፡ በእርሱ ፡ ፊት ፡ ይን
፲፮ በረከካል ። ግማሹን ፡ በእሳት ፡ ያቃጥላል ÷
በዚያ ፡ በግማሹ ፡ ሥጋ ፡ ይበላል ÷ ሥጋም ፡
ይጠብሰበትና ፡ ይጠግባል ፤ ይሞቃልና ፡—
እሰይ ፡ ሞቅሁ ÷ እሳቱን ፡ አይቻለሁ ፡ ይላል ።
፲፯ የቀረውንም ፡ እንጨት ፡ አምላክ ፡ አድርጎ ፡
ምስል ፡ ይቀርጽበታል ፤ በፊቱም ፡ ተጐንብሶ ፡
ይሰግዳል ፡ ወደ ፡ እርሱም ፡ እየጸለየ ፡— አም
ላኬ ፡ ነህና ፡ አድነኝ ፡ ይላል ።

፲፰ አያውቁም ÷ አያስቡም ፤ እንዳያዩ ፡ ዓይኖቻ
ቸውን ÷ እንዳያስተውሉም ፡ ልቦቻቸውን ፡
፲፱ ጨፍነዋል ። በልቡም ፡ ማንም ፡ አያስብም ፡—
ግማሽዋን ፡ በእሳት ፡ አቃጥያለሁ ÷ በፍምዋም ፡
ላይ ፡ እንጀራን ፡ ጋግሬአለሁ ÷ ሥጋም ፡ ጠብሼ ፡

በልቻለሁ ፤ የቀረውንም ፡ እስጸያፊ ፡ ነገር ፡ አደ
ርጋለሁን ? ለዛፍስ ፡ ግንድ ፡ እሰግዳለሁን ? እን
ዲልም ፡ እውቀትና ፡ ማስተዋል ፡ የለውም ።
፳፤ አመድ ፡ ይበላል ፥ የተታለለ ፡ ልብ ፡ አስቶታል ፥
ነፍሱን ፡ ለማዳን ፡ አይችልም ፥ ወይም ፡—
በቀኜ ፡ እጄ ፡ ሐሰት ፡ አለ ፡ አይልም ።
፳፩፤ ያዕቆብ ፡ ሆይ ፥ አንተም ፡ እስራኤል ፥ ባሪ
ያዬ ፡ ነህና ፡ ይህን ፡ አስብ ፤ እኔ ፡ ሠርቼሃለሁ ፡
አንተም ፡ ባሪያዬ ፡ ነህ ፤ እስራኤል ፡ ሆይ ፥
፳፪፤ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ያልተረሳ ፡ ትሆናለህ ። መተላለ
ፍህን ፡ እንደ ፡ ደመና ፥ ኃጢአትህንም ፡ እንደ ፡
ጭጋግ ፡ ደምስሼአለሁ ፤ ተቤዥቼሃለሁና ፡ ወደ ፡
፳፫፤ እኔ ፡ ተመለስ ። ሰማያት ፡ ሆይ ፥ እግዚአብ
ሔር ፡ አድርጎታልና ፡ ዘምሩ ፤ እግዚአብሔር ፡
ያዕቆብን ፡ ተቤዥቶአልና ፥ በእስራኤልም ፡
ዘንድ ፡ ይከበራልና ፡ አንተ ፡ የምድር ፡ ጥልቅ ፡
ሆይ ፥ ጩኽ ፤ እናንተም ፡ ተራሮች ፡ አንተም ፡
ዱር ፡ በአንተም ፡ ያለ ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፥ እልል ፡
በሉ ።
፳፬፤ ከማኅፀን ፡ የሠራህ ፥ የሚቤዥህ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ሁሉን ፡ የፈጠርሁ ፥
ሰማያትን ፡ ለብቻዬ ፡ የዘረጋሁ ፡ ምድርንም ፡
ያጸናሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ ከእኔ ፡
፳፭፤ ጋር ፡ ማን ፡ ነበረ ? የሐሰተኞችን ፡ ምልክት ፡
ከንቱ ፡ አደርጋለሁ ፥ ምዋርተኞችንም ፡ አሳብዳ
ለሁ ፥ ጥበበኞቹንም ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ እመልሳለሁ ፡
፳፮፤ እውቀታቸውንም ፡ ስንፍና ፡ አደርጋለሁ ፤ የባ
ሪያዬን ፡ ቃል ፡ አጸናለሁ ፥ የመልእክተኞቼ
ንም ፡ ምክር ፡ እፈጽማለሁ ፤ ኢየሩሳሌምን ፡—
የሰው ፡ መኖሪያ ፡ ትሆኚለሽ ፥ የይሁዳንም ፡
ከተሞች ፡— ትታነጻላችሁ ፡ ፍራሾቻችሁንም ፡
፳፯፤ አቆማለሁ ፡ እላለሁ ፤ ቀላዩንም ፡— ደረቅ ፡
ሁን ፥ ፈሳሾችህንም ፡ አደርቃለሁ ፡ እላለሁ ፤
፳፰፤ ቂሮስንም ፡— እርሱ ፡ እረኛዬ ፡ ነው ፤ እርሱም ፡
ኢየሩሳሌምን ፡— ትታነጺያለሽ ፡ ቤተ ፡ መቅ
ደስም ፡ ይመሠረታል ፡ ብሎ ፡ ፈቃዴን ፡ ሁሉ ፡
ይፈጽማል ፡ እላለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፭ ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ ለቀባሁት ፥ አሕዛብንም ፡
በፊቱ ፡ አስገዛ ፡ ዘንድ ፡ የነገሥታትንም ፡ ወገብ ፡
እፈታ ፡ ዘንድ ፥ በሮቹም ፡ እንዳይዘጉ ፡ መዝ
ጊያዎቹን ፡ በፊቱ ፡ እከፍት ፡ ዘንድ ፥ ቀኝ ፡
እጁን ፡ ለያዝሁት ፡ ለቂሮስ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
፪፤ በፊትህ ፡ እሄዳለሁ ፡ ተራሮችንም ፡ ትክክል ፡
አደርጋለሁ ፥ የናሱንም ፡ ደጆች ፡ እሰብራለሁ ፡
የብረቱንም ፡ መወርወሪያዎች ፡ እቈርጣለሁ ፤
፫፤ በስምህም ፡ የምጠራህ ፡ የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እኔ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡
ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ በጨለማ ፡ የነበረችውን ፡
መዝገብ ፡ በስውርም ፡ የተደበቀችውን ፡ ሀብት ፡
፬፤ እሰጥሃለሁ ። ስለ ፡ ባሪያዬ ፡ ስለ ፡ ያዕቆብ ፥
ስለ ፡ መረጥሁትም ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡ ብዬ ፡ በስ
ምህ ፡ ጠርቼሃለሁ ፤ በቍልምጫ ፡ ስምህ ፡ ጠራ
ሁህ ፥ አንተ ፡ ግን ፡ አላወቅኸኝም ። እኔ ፡ እግ ፭፤፮፤
ዚአብሔር ፡ ነኝ ፡ ከእኔም ፡ ሌላ ፡ ማንም ፡ የለም ፤
ከእኔም ፡ በቀር ፡ አምላክ ፡ የለም ፤ በፀሐይ ፡ መው
ጫና ፡ በምዕራብ ፡ ያሉ ፡ ከእኔ ፡ በቀር ፡ ማንም ፡
ሌላ ፡ እንደሌለ ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ አስታጠቅሁህ ፥
አንተ ፡ ግን ፡ አላወቅኸኝም ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡
ነኝ ፥ ከእኔም ፡ ሌላ ፡ ማንም ፡ የለም ። ብርሃንን ፡ ፯፤
ሠራሁ ፥ ጨለማውንም ፡ ፈጠርሁ ፤ ደኅንነትን ፡
እሠራለሁ ፥ ክፉትንም ፡ እፈጥራለሁ ፤ እነዚ
ህን ፡ ሁሉ ፡ ያደረግሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ እኔ ፡
ነኝ ።

፰፤ እናንተ ፡ ሰማያት ፡ ከላይ ፡ አንጠባጥቡ ፡ ደመ
ናትም ፡ ጽድቅን ፡ ያዝንቡ ፤ ምድርም ፡ ትከፈት ፡
መድኃኒትንም ፡ ታብቅል ፥ ጽድቅም ፡ በአንድ
ነት ፡ ይብቀል ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈጥሬዋ
ለሁ ።

፱፤ ከሠሪው ፡ ጋር ፡ ለሚታገል ፡ ወዮለት ! በም
ድር ፡ ሸክላዎች ፡ መካከል ፡ ያለ ፡ ሸክላ ፡ ነው ።
ጭቃ ፡ ሠሪውን ፡— ምን ፡ ትሠራለህ ? ወይስ ፡
፲፤ ሥራህ ፡— እጅ ፡ የለውም ፡ ይላልን ? አባትን ፡—
ምን ፡ ወልደሃል ? ወይም ፡ ሴትን ፡— ምን ፡ አማ
ጥሽ ? ለሚል ፡ ወዮ !

፲፩፤ የእስራኤል ፡ ቅዱስ ፡ ሠሪውም ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ስለሚመጣው ፡ ነገር ፡
ጠይቁኝ ፥ ስለ ፡ ልጆቼና ፡ ስለ ፡ እጄ ፡ ሥራም ፡
፲፪፤ እዘዙኝ ። እኔ ፡ ምድርን ፡ ሠርቻለሁ ፡ ሰውንም ፡
በእርስዋ ፡ ላይ ፡ ፈጥሬአለሁ ፤ እኔ ፡ በእጄ ፡ ሰማ
ያትን ፡ ዘርግቼአለሁ ፥ ሠራዊታቸውንም ፡ ሁሉ ፡
፲፫፤ አዝዣለሁ ። እኔ ፡ በጽድቅ ፡ አስነሥቼዋለሁ ፡
መንገዱንም ፡ ሁሉ ፡ አቀናለሁ ፤ እርሱ ፡ ከተማ
ዬን ፡ ይሠራል ፥ በዋጋም ፡ ወይም ፡ በደመወዝ ፡
ሳይሆን ፡ ምርኮኞቼን ፡ ያወጣል ፥ ይላል ፡ የሠ
ራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፲፬፤ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የግ
ብጽ ፡ ድካምና ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንግድ ፡ ቁመተ ፡
ረጅሞችም ፡ የሳባ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ያል
ፋሉ ! ለአንተም ፡ ይሆናሉ ፡ እጆቻቸውም ፡
ታስረው ፡ ይከተሉሃል ፤ በፊትህም ፡ ያልፋሉ ፥
ለአንተም ፡ እየሰገዱ ፡— በእውነት ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በአንተ ፡ አለ ፥ ከእርሱም ፡ ሌላ ፡ አም
፲፭፤ ላክ ፡ የለም ፡ ብለው ፡ ይለምኑሃል ። የእስራኤል ፡
አምላክ ፡ መድኃኒት ፡ ሆይ ፥ በእውነት ፡ አንተ ፡
፲፮፤ ራስህን ፡ የምትሰውር ፡ አምላክ ፡ ነህ ። ሁሉም ፡
ያፍራሉ ፡ ይዋረዱማል ፥ ጣዖታትንም ፡ የሚ
ሠሩ ፡ በአንድነት ፡ ወደ ፡ ውርደት ፡ ይሄዳሉ ።
፲፯፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ እስራኤልን ፡ በዘላለማዊ ፡
መድኃኒት ፡ ያድነዋል ፥ እናንተም ፡ ለዘላለም ፡
አታፍሩምና ፡ አትዋረዱም ።

፲፰፤ ሰማያትን ፡ የፈጠረ ፡ እግዚአብሔር ፥ እር
ሱም ፡ ምድርን ፡ የሠራና ፡ ያደረገ ፡ ያጸናትም ፥
መኖሪያም ፡ ልትሆን ፡ እንጂ ፡ ለከንቱ ፡ እንድ
ትሆን ፡ ያልፈጠራት ፡ አምላክ ፥ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ፡ ከእኔም ፡
፲፱፤ በቀር ፡ ሌላ ፡ የለም ። በስውር ፡ ወይም ፡ በጨ

ለማ ፡ ምድር ፡ ስፍራ ፡ አልተናገርሁም ፤ ለያዕ
ቆብ ፡ ዘር ፡— በከንቱ ፡ ፈልጉኝ ፡ አላልሁም ፤
እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጽድቅን ፡ እናገራለሁ ፡
፳ ቅንንም ፡ አወራለሁ ። እናንተ ፡ ከአሕዛብ ፡
ወገን ፡ ሆናችሁ ፡ ያመለጣችሁ ÷ ተሰብስባችሁ ፡
ኑ ፡ በአንድነትም ፡ ቅረቡ ፤ የተቀረጸውን ፡ የምስ
ላቸውን ፡ እንጨት ፡ የሚሸከሙና ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡
ወደማይችል ፡ አምላክ ፡ የሚጸልዩ ፡ እውቀት ፡
፳፩ የላቸውም ። ይናገሩ ፡ ይቅረቡም ፡ በአንድነ
ትም ፡ ይማከሩ ፤ ከጥንቱ ፡ ይህን ፡ ያሳየ ፡ ከቀድ
ሞስ ፡ የተናገረ ፡ ማን ፡ ነው ? ያሳየሁም ፡ የተና
ገርሁም ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አይደለሁምን ?
ከእኔም ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ አምላክ ፡ የለም ፤ እኔ ፡
ጻድቅ ፡ አምላክና ፡ መድኃኒት ፡ ነኝ ÷ ከእኔም ፡
፳፪ በቀር ፡ ማንም ፡ የለም ። እናንተ ፡ የምድር ፡
ዳርቻ ፡ ሁሉ ÷ እኔ ፡ አምላክ ፡ ነኝና ÷ ከእኔም ፡
በቀር ፡ ሌላ ፡ የለምና ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ዘወር ፡ በሉ ፡
፳፫ ትድኑማላችሁ ። ቃሌ ፡ ከአፌ ፡ በጽድቅ ፡ ወጥ
ቷለች ÷ አትመለስም ፡— ጕልበት ፡ ሁሉ ፡ ለእኔ ፡
ይንበረከካል ÷ ምላስም ፡ ሁሉ ፡ በእኔ ፡ ይምላል ፡
፳፬ ብዬ ፡ በራሴ ፡ ምያለሁ ። ስለ ፡ እኔም ፡— በእግ
ዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ብቻ ፡ ጽድቅና ፡ ኃይል ፡
አለ ÷ ወደ ፡ እርሱም ፡ ሰዎች ፡ ይመጣሉ ÷
በእርሱም ፡ ላይ ፡ የተቈጡ ፡ ሁሉ ፡ ያፍራሉ ።
፳፭ የእስራኤልም ፡ ዘር ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ይጸድቃሉ ÷ ይመከሉም ፡ ይበላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፮ ።

፩ ቤል ፡ ተዋረደ ÷ ናባው ፡ ተሰባበረ ፤ ጣዖቶቻ
ቸው ፡ በእንስሳና ፡ በከብት ፡ ላይ ፡ ተጭነዋል ፤
ሸክሞቻችሁ ፡ ለደካማ ፡ እንስሳ ፡ ከባድ ፡ ጭነት ፡
፪ ሆነዋል ። ተጐነበሱ ፡ በአንድነትም ፡ ተዋረዱ ፤
ሸክሙን ፡ ለማዳን ፡ አልቻሉም ÷ ራሳቸው ፡ ግን ፡
ተማረኩ ።

፫ እናንተ ፡ የያዕቆብ ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ የእስራኤ
ልም ፡ ቤት ፡ ቅሬታ ፡ ሁሉ ÷ ከሆድ ፡ ያነሣኋ
ችሁ ፡ ከማኅፀንም ፡ የተሸከምኋችሁ ÷ ስሙኝ ።
፬ እስከ ፡ ሽምግልና ፡ ድረስ ፡ እኔ ፡ ነኝ ÷ እስከ ፡
ሽበትም ፡ ድረስ ፡ እሸከማችኋለሁ ፤ እኔ ፡ ሠር
ቻለሁ ፡ እኔም ፡ እነሣለሁ ፤ እኔ ፡ እሸከማለሁ ፡
፭ እኔም ፡ አድናለሁ ። በማን ፡ ትመስሉኛላችሁ ?
ከማንስ ፡ ጋር ፡ ታስተካክሉኛላችሁ ? እንመሳ
ሰል ፡ ዘንድ ፡ ከማን ፡ ጋር ፡ ታስተያዩኛላችሁ ?
፮ ወርቁን ፡ ከከረጢት ፡ የሚያፈስሱ ፡ ብሩንም ፡ በሚ
ዛን ፡ የሚመዝኑ ፡ እነርሱ ፡ አንጥረኛውን ፡ ይቀ
ጥራሉ ÷ እርሱም ፡ አምላክ ፡ አድርጎ ፡ ይሠራ
ዋል ፤ ለዚያም ፡ ይጐነበሱለታል ፡ ይሰግዱለት
፯ ማል ። በጫንቃቸው ፡ ላይ ፡ አንሥተው ፡ ይሸ
ከሙታል ፡ በስፍራውም ፡ ያደርጉታል ÷ በዚ
ያም ፡ ይቆማል ÷ ከስፍራውም ፡ ፈቀቅ ፡ አይ
ልም ፤ ሰውም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቢጮኽ ፡ አይሰ
ማውም ፡ ከመከራውም ፡ አያድነውም ።

፰ ይህን ፡ አስቡና ፡ አልቅሱ ፤ ተላላፊዎች ፡ ሆይ ÷
፱ ንስሐ ፡ ግቡ ÷ ልባችሁንም ፡ መልሱ ። እኔ ፡
አምላክ ፡ ነኝና ÷ ሌላም ፡ የለምና ፡ የቀድሞ
ውን ፡ የጥንቱን ፡ ነገር ፡ አስቡ ፤ እኔ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ነኝ ፡ እንደ ፡ እኔም ፡ ያለ ፡ ማንም ፡ የለም ።
፲ በመጀመሪያ ፡ መጨረሻውን ÷ ከጥንትም ፡ ያል
ተደረገውን ፡ እነግራለሁ ፤ ምክሬ ፡ ትጸናለች ፡
፲፩ ፈቃዴንም ፡ ሁሉ ፡ እፈጽማለሁ ፡ እላለሁ ። ከም
ሥራቅ ፡ ነጣቂ ፡ ወፍን ÷ ከሩቅም ፡ አገር ፡ ምክ
ሬን ፡ የሚያደርገውን ፡ ሰው ፡ እጠራዋለሁ ።
ተናግሬአለሁ ፡ እፈጽምማለሁ ፤ አስቤአለሁ ፡
አደርግማለሁ ።

፲፪ እናንተ ፡ ከጽድቅ ፡ የራቃችሁ ፡ እልከኞች ÷
፲፫ ስሙኝ ፤ ጽድቄን ፡ አቀርባለሁ ÷ አይርቅም ፡
መድኃኒቴም ፡ አይዘገይም ፤ ከጽዮን ፡ ለክብር ፡
እንዲሆን ፡ መድኃኒትን ፡ ለእስራኤል ፡ ሰጥቻ
ለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፯ ።

፩ አንቺ ፡ ድንግል ፡ የባቢሎን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷
ውረጂ ፡ በትቢያም ፡ ላይ ፡ ተቀመጪ ፤ የከለዳ
ውያን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ቅል
ጣናምና ፡ ቅምጥል ፡ አትባይምና ፡ ያለ ፡ ዙፋን ፡
፪ በመሬት ፡ ላይ ፡ ተቀመጪ ። ወፍጮ ፡ወስደሽ ፡
ዱቄትን ፡ ፍጪ ፤ መሸፈኛሽን ፡ አውጪ ፡ ረጅ
ሙንም ፡ ልብስሽን ፡ አውልቀሽ ፡ ጣዩውን ፤ ባት
፫ ሽን ፡ ግለጪ ÷ ወንዙን ፡ ተሻገሪ ። ኀፍረተ ፡
ሥጋሽ ፡ ይገለጣል ፡ እፍረትሽም ፡ ይታያል ፤
፬ እኔ ፡ እበቀላለሁ ÷ ለማንም ፡ አልራራም ። ታዳ
ጊያችን ÷ ስሙ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
፭ ሔር ÷ የእስራኤል ፡ ቅዱስ ፡ ነው ። የከለዳው
ያን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ከዚህ ፡ በኋላ ፡— የመን
ግሥታት ፡ እመቤት ፡ አትባይምና ፡ ዝም ፡ ብለሽ ፡
ተቀመጪ ፡ ወደ ፡ ጨለማም ፡ ውስጥ ፡ ግቢ ።
፮ በሕዝቤ ፡ ላይ ፡ ተቈጥቼ ፡ ነበር ፡ ርስቴንም ፡
አረከስሁ ፡ በእጅሽም ፡ አሳልፌ ፡ ሰጠኋቸው ፤
ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ምሕረት ፡ አላደረግሽም ÷ በሽ
ማግሌዎቻቸው ፡ ላይ ፡ ቀንበርሽን ፡ እጅግ ፡ አከ
፯ ብደሻል ። አንቺም ፡— እኔ ፡ ለዘላለም ፡ እመ
ቤት ፡ እሆናለሁ ፡ ብለሻል ፤ ይህንም ፡ በልብሽ ፡
አላደረግሽም ፡ ፍጻሜውንም ፡ አላሰብሽም ።

፰ አሁንም ፡ አንቺ ፡ ቅምጥል ፡ ተዘልለሽ ፡ የም
ትቀመጪ ÷ በልብሽም ፡— እኔ ፡ ነኝ ፡ ከእኔም ፡
በቀር ፡ ሌላ ፡ የለም ፤ መበለትም ፡ ሆኜ ፡ አልኖ
ርም ፡ የወላድ ፡ መካንነትንም ፡ አላውቅም ፡ የም
፱ ትዪ ፡ ይህን ፡ ስሚ ፤ አሁን ፡ ግን ፡ በአንድ ፡
ቀን ፡ እነዚህ ፡ ሁለት ፡ ነገሮች ÷ የወላድ ፡ መካ
ንነትና ፡ መበለትነት ÷ በድንገት ፡ ይመጡብ
ሻል ፤ ስለ ፡ መተቶችሽ ፡ ብዛትና ፡ ስለ ፡ አስማ
ቶችሽ ፡ ጽናት ፡ ፈጽመው ፡ ይመጡብሻል ።
፲ በክፋትሽ ፡ ታምነሻል ፤ የሚያየኝ ፡ የለም ፡
ብለሻል ፤ ጥበብሽና ፡ እውቀትሽ ፡ አታልለው
ሻል ÷ በልብሽም ፡— እኔ ፡ ነኝ ፡ ከእኔም ፡ በቀር ፡
፲፩ ሌላ ፡ የለም ፡ ብለሻል ። ስለዚህ ፡ ምክንያት ፡
ክፉ ፡ ነገር ፡ ይመጣብሻል ÷ በምዋርትሽም ፡ እን
ዴት ፡ እንደምታርቂው ፡ አታውቂም ፤ ጉዳት ፡

ይወድቅብሻል ፡ ታስወግጅውም ፡ ዘንድ ፡ አይቻልሽም ፤ የማታውቂያትም ፡ ጕስቍልና ፡ ድንገት ፡ ትመጣብሻለች ።
፲፪ ምናልበትም ፡ መጠቀም ፡ ትችዪ ፡ ወይም ፡ ታስደነግጪ ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ ከአስማቶችሽና ፡ ከሕፃንነትሽ ፡ ጀምረሽ ፡ ከደከምሽበት ፡ ከመተ
፲፫ ቶችሽ ፡ ብዛት ፡ ጋር ፡ ቁሚ ። በምክርሽ ፡ ብዛት ፡ ደክመሻል ፤ አሁንም ፡ የሰማይን ፡ ከዋክብት ፡ የሚቈጥሩ ÷ ከዋክብትንም ፡ የሚመለከቱ ÷ በየመባቻውም ፡ የሚመጣውን ፡ ነገር ፡ የሚናገሩ ፡ ተነሥተው ፡ ከሚመጣብሽ ፡ ነገር ፡ ያድኑሽ ።
፲፬ እነሆ ÷ እንደ ፡ እብቅ ፡ ይሆናሉ ÷ እሳትም ፡ ያቃጥላቸዋል ፡ ሰውነታቸውንም ፡ ከነበልባል ፡ ኃይል ፡ አያድኑም ፤ እርሱም ፡ ሰው ፡ እንደሚሞቀው ፡ ፍም ÷ ወይም ፡ በፊቱ ፡ ሰው ፡ እንደ
፲፭ ሚቀመጥበት ፡ እሳት ፡ ያለ ፡ አይደለም ። የደከምሽባቸው ፡ ነገሮች ፡ እንዲህ ፡ ይሆኑብሻል ፤ ከሕፃንነትሽ ፡ ጀምረው ፡ ከአንቺ ፡ ጋር ፡ ይነግዱ ፡ የነበሩ ፡ እያንዳንዳቸው ፡ ወደ ፡ ስፍራቸው ፡ ይሄዳሉ ÷ የሚያድንሽም ፡ የለም ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፰ ።

፩ እናንተ ፡ በእስራኤል ፡ ስም ፡ የተጠራችሁ ፡ ከይሁዳም ፡ ውኆች ፡ የወጣችሁ ÷ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የምትምሉ ÷ በእውነት ፡ ሳይሆን ፡ በጽድቅም ፡ ሳይሆን ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡
፪ የምትጠሩ ÷ በቅድስት ፡ ከተማ ፡ ስም ፡ የተጠራችሁ ÷ ስሙም ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሚባል ፡ በእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የምትደገፉ ÷ የያዕቆብ ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ ይህን ፡ ስሙ ።
፫ የቀድሞውን ፡ ነገር ፡ ከጥንት ፡ ተናግሬአለሁ ÷ ከአፌም ፡ ወጥቶአል ፡ አሳይቼውማለሁ ፤ ድን
፬ ገት ፡ አድርጌዋለሁ ፡ ተፈጽሞማል ። አንተ ፡ እልከኛ ÷ አንገትህም ፡ የብረት ፡ ጅማት ÷ ግም
፭ ባርህም ፡ ናስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አውቄአለሁ ፤ ስለ ዚህ ÷ አንተ ፡— ጣዖቴ ፡ ይህን ፡ አድርጎአል ÷ የተቀረጸው ፡ ምስሌና ፡ ቀልጦ ፡ የተሠራው ፡ ምስሌ ፡ ይህን ፡ አዘዙኝ ፡ እንዳትል ÷ አስቀድሜ ፡ ነግሬህ ፡ ነበር ፡ ሳይሆንም ፡ አሳይቼህ ፡
፮ ነበር ። ሰምተሃል ፤ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ተመልከት ፤ እናንተም ፡ የምትናገሩት ፡ አይደላችሁምን ? የተሰወሩትን ፡ ያላወቅሃቸውንም ፡ አዲሶች ፡ ነገሮችን ፡ ከዚህ ፡ ጀምሬ ፡ አሳይቼሃለሁ ።
፯ እነርሱም ፡ አሁን ፡ እንጂ ፡ ከጥንት ፡ አልተፈጠሩም ፤ አንተም ፡— እነሆ ÷ አውቄአቸዋለሁ ፡ እንዳትል ፡ ከዛሬ ፡ በፊት ፡ አልሰማሃቸውም ።
፰ አልሰማህም ÷ አላወቅህም ÷ ጆሮህ ፡ ከጥንት ፡ አልተከፈተችም ፤ አንተ ፡ ፈጽሞ ፡ ወንጀለኛ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ ከማኅፀንም ፡ ጀምረህ ፡ ተላላፊ ፡ ተብለህ ፡ እንደ ፡ ተጠራህ ፡ አውቄአለሁና ።
፱ ስለ ፡ ስሜ ፡ ቍጣዬን ፡ አዘገያለሁ ÷ እንዳላጠፋ
፲ ህም ፡ ስለ ፡ ምስጋናዬ ፡ እታገሣለሁ ። እነሆ ÷ አንጥሬሃለሁ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ብር ፡ አይደ
፲፩ ለም ፤ በመከራም ፡ እቶን ፡ ፈትኜሃለሁ ። ስለ ፡ እኔ ÷ ስለ ፡ ራሴ ፡ አደርገዋለሁ ፡ ስሜ ፡ ተነቅፎአልና ፤ ክብሬንም ፡ ለሌላ ፡ አልሰጥም ።
፲፪ ያዕቆብ ፡ ሆይ ÷ የጠራሁህም ፡ እስራኤል ፡ ሆይ ÷ ስማኝ ፤ እኔ ፡ ነኝ ፤ እኔ ፡ ፊተኛው ፡ ነኝ ፡ እኔም ፡ ኋለኛው ፡ ነኝ ።
፲፫ እጄም ፡ ምድርን ፡ መሠርታለች ፡ ቀኜም ፡ ሰማያትን ፡ ዘርግታለች ፤ በጠራኋቸው ፡ ጊዜ ፡ በአንድነት ፡ ይቆማሉ ።
፲፬ እናንተ ፡ ሁሉ ÷ በአንድነት ፡ ተሰብሰባችሁ ፡ ስሙ ፤ ከእነርሱ ፡ ይህን ፡ የተናገረ ፡ ማን ፡ ነው ? እግዚአብሔር ፡ የወደደው ፡ ፈቃዱን ፡ በባቢሎን ፡ ላይ ፡ ያደርጋል ÷ ክንዱም ፡ በከለዳውያን ፡ ላይ ፡ ይሆናል ።
፲፭ እኔ ፡ ራሴ ፡ ተናግሬአለሁ ፤ እኔ ፡ ጠርቼዋለሁ ፤ አምጥቼዋለሁ ÷ መንገዱም ፡ ትከናወንለታለች ።
፲፮ ወደ ፡ እኔ ፡ ቅረቡ ፡ ይህንም ፡ ስሙ ፤ እኔ ፡ ከጥንት ፡ ጀምሬ ፡ በስውር ፡ አልተናገርሁም ፤ ከሆነበት ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ እኔ ፡ በዚያ ፡ ነበርሁ ÷ አሁንም ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርና ፡ መንፈሱ ፡ ልከውኛል ።
፲፯ ታዳጊህ ÷ የእስራኤል ፡ ቅዱስ ÷ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እኔ ፡ የሚረባህን ፡ ነገር ፡ የማስተምርህ ፡ በምትሄድበትም ፡ መንገድ ፡ የምመራህ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ።
፲፰ ትእዛዜን ፡ ብትሰማ ፡ ኖሮ ÷ ሰላምህ ፡ እንደ ፡ ወንዝ ፡ ጽድቅህም ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ ሞገድ ፡ በሆነ ፡ ነበር ፤
፲፱ ዘርህም ፡ እንደ ፡ አሸዋ ፡ የሆድህም ፡ ትውልድ ፡ እንደ ፡ ምድር ፡ ትቢያ ፡ በሆነ ፡ ነበር ÷ ስሙም ፡ ከፊቴ ፡ ባልጠፋና ፡ ባልፈረሰ ፡ ነበር ።
፳ ከባቢሎን ፡ ውጡ ፡ ከከለዳውያንም ፡ ኰብልሉ ፤ በእልልታ ፡ ድምፅ ፡ ተናገሩ ፡ ይህንም ፡ ንገሩ ፡ እስከ ፡ ምድርም ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ አውሩና ፡— እግዚአብሔር ፡ ባሪያውን ፡ ያዕቆብን ፡ ታድጎታል ፡ በሉ ።
፳፩ በምድረ ፡ በዳ ፡ በኩል ፡ በመራቸው ፡ ጊዜ ፡ አልተጠሙም ፤ ውኃንም ፡ ከዓለቱ ፡ ውስጥ ፡ አፈለቀላቸው ÷ ዓለቱንም ፡ ሰነጠቀ ፡ ውኃውም ፡ ፈሰሰ ።
፳፪ ለክፉዎች ፡ ሰላም ፡ የላቸውም ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፱ ።

፩ ደሴቶች ፡ ሆይ ÷ ስሙኝ ÷ እናንተም ፡ በሩቅ ፡ ያላችሁ ፡ አሕዛብ ÷ አድምጡ ፤ እግዚአብሔር ፡ ከማኅፀን ፡ ጠርቶኛል ÷ ከእናቴም ፡ ሆድ ፡
፪ ጀምሮ ፡ ስሜን ፡ አንሥቶአል ፤ አፌንም ፡ እንደ ፡ ተሳለ ፡ ሰይፍ ፡ አድርጎአል ÷ በእጁ ፡ ጥላ ፡ ሰውሮኛል ፤ እንደ ፡ ተሳለ ፡ ፍላጻም ፡ አድርጎኛል ÷
፫ በሰገባውም ፡ ውስጥ ፡ ሸሽጎኛል ። እርሱም ፡— እስራኤል ፡ ሆይ ÷ አንተ ፡ ባሪያዬ ፡ ነህ ፡ በአን
፬ ተም ፡ እከበራለሁ ፡ አለኝ ። እኔ ፡ ግን ፡— በከንቱ ፡ ደከምሁ ÷ ምንም ፡ ጥቅም ፡ ለሌለውና ፡ ለከንቱ ፡ ጕልበቴን ፡ ፈጀሁ ፤ ፍርዴ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ÷ ዋጋዬም ፡ በአምላኬ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ አልሁ ።
፭ አሁንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዓይን ፡ ክቡር

ለሁና ፥ አምላኬም፡ ኃይል፡ ሆኖኛልና፡ ያዕቆብን፡ ወደ፡ እርሱ፡ እንድመልስ፡ እስራኤልንም፡ ወደ፡ እርሱ፡ እንድሰበስብ፡ ባሪያ፡ እሆ ነው፡ ዘንድ፡ ከማኅፀን፡ ጀምሮ፡ የሠራኝ፡ እግ

፮፤ ዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል ። እርሱም፡—የያዕቆብን፡ ነገዶች፡ እንድታስነሣ፡ ከእስራኤልም፡ የዳኑትን፡ እንድትመልስ፡ ባሪያዬ፡ ትሆን፡ ዘንድ፡ እጅግ፡ ቀላል፡ ነገር፡ ነውና፡ እስከ፡ ምድር፡ዳር፡ድረስ፡መድኃኒት፡ትሆን፡ዘንድ፡ ለአሕዛብ፡ብርሃን፡አድርጌ፡ሰጥቼሃለሁ፡ ይላል ።

፯፤ የእስራኤል፡ ታዳጊ፡ ቅዱሱም ፥ እግዚአብሔር ፥ ሰዎች፡ ለሚንቁት፡ ሕዝብም፡ ለሚጠላው፡ ለገዦዎች፡ ባሪያ፡ እንዲህ፡ ይላል፡— ስለ፡ ታማኙ፡ ስለ፡ እግዚአብሔር፡ ስለ፡ መረጠህም፡ ስለ፡ እስራኤል፡ ቅዱስ፡ ነገሥታት፡ አይተው፡ ይነሣሉ ፥ መሳፍንትም፡ አይተው፡ ይሰግዳሉ ።

፰፤ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡— በተወደደ፡ ጊዜ፡ ሰምቼሃለሁ ፥ በመድኃኒትም፡ ቀን፡ ረድቼሃለሁ ፤ እጠብቅህማለሁ ፥ ምድርንም፡ ታቀና፡ ዘንድ ፥ ውድማ፡ የሆኑትንም፡

፱፤ ርስቶች፡ ታወርስ፡ ዘንድ ፥ የተጋዙትንም፡— ውጡ፡ በጨለማም፡ የተቀመጡትን፡— ተገለጡ፡ ትል፡ ዘንድ፡ ቃል፡ ኪዳን፡ አድርጌ፡ ለሕዝቡ፡ ሰጥቼሃለሁ ። በመንገድም፡ ላይ፡ ይሰማራሉ ፥ ማሰማርያቸውም፡ በወና፡ ኮረብታ፡

፲፤ ሁሉ፡ላይ፡ ይሆናል ። የሚራራላቸውም፡ ይመራቸዋልና ፥ በውኃም፡ ምንጮች፡ በኩል፡ ይነዳቸዋልና፡ አይራቡም ፥ አይጠሙም ፥ ትኩሳት፡ ወይም፡ ፀሐይ፡ አይጐዳቸውም ።

፲፩፤ ተራሮቼንም፡ ሁሉ፡ መንገድ፡ አደርጋለሁ ፥

፲፪፤ ጎዳኖቼም፡ ከፍ፡ ከፍ፡ ይላሉ ። እነሆ ፥ እነዚህ፡ ከሩቅ ፥ እነሆም ፥ እነዚህ፡ ከሰሜንና፡ ከምዕራብ ፥ እነዚህም፡ ከሲኒም፡ አገር፡ ይመ

፲፫፤ ጣሉ ። እግዚአብሔር፡ ሕዝቡን፡ አጽናንቶአልና ፥ ለችግረኞቹም፡ ራርቶአልና፡ ሰማያት፡ ሆይ ፥ ዘምሩ ፥ ምድር፡ ሆይ ፥ ደስ፡ ይበልሽ፡ ተራሮችም፡ ሆይ ፥ እልል፡ በሉ ።

፲፬፤ ጽዮን፡ ግን፡— እግዚአብሔር፡ ትቶኛል፡

፲፭፤ ጌታም፡ ረስቶኛል፡ አለች ። በውኑ፡ ሴት፡ ከማኅፀንዋ፡ ለተወለደው፡ ልጅ፡ እስከማትራራ፡ ድረስ፡ ሕፃንዋን፡ ትረሳ፡ ዘንድ፡ ትችላለችን? አዎን ፥ እርስዋ፡ ትረሳ፡ ይሆናል ፥ እኔ፡

፲፮፤ ግን፡ አልረሳሽም ። እነሆ ፥ እኔ፡ በእጄ፡ መዳፍ፡ ቀርጬሻለሁ ፥ ቅጥሮችሽም፡ ሁልጊዜ፡ በፊቴ፡

፲፯፤ አሉ ። ልጆችሽ፡ ይፈጥናሉ ፤ ያፈረሱሽና፡

፲፰፤ ያወደሙሽ፡ ከአንቺ፡ ዘንድ፡ ይወጣሉ ። ዓይንሽን፡ አንሥተሽ፡ በዙሪያሽ፡ ተመልከቺ ፤ እነዚህ፡ ሁሉ፡ ተሰብስበው፡ ወደ፡ አንቺ፡ ይመጣሉ ። እኔ፡ ሕያው፡ ነኝና፡ እነዚህን፡ ሁሉ፡ እንደ፡ጌጥ፡ትለብሻቸዋለሽ ፥ እንደ፡ ሙሽራም፡ ትጐናጸፊአቸዋለሽ ፥ ይላል፡ እግዚአብሔር ።

፲፱፤ በድማሽና፡ ውድማሽ፡ ወናም፡ የሆነው፡ ምድርሽ፡ ከሚኖሩብሽ፡ የተነሣ፡ ዛሬ፡ ጠባብ፡ ትሆ

፳፤ ናለችና ፥ የዋጡሽም፡ ይርቃሉና ። የወላድ፡ መካን፡ ከሆንሽ፡ በኋላ፡ የተወለዱልሽ፡ ልጆችሽ፡ በጆሮሽ፡— ስፍራ፡ ጠብቦኛልና፡ እቀ

፳፩፤ መጥ፡ ዘንድ፡ ቦታ፡ አስፈልገኝ፡ ይላሉ ። አንቺም፡ በልብሽ፡— የወላድ፡ መካን፡ ሆኜ ለሁና ፥ እኔም፡ ብቻዬን፡ ተሰድጄ አለሁና፡ ተቅበዝብዤ አለሁምና፡ እነዚህን፡ ማን፡ ወለደልኝ? እነዚህንስ፡ ማን፡ አሳደጋቸው? እነሆ ፥ ብቻዬን፡ ቀርቼ፡ ነበር ፤ እነዚህስ፡ ወዴት፡ ነበሩ? ትያለሽ ።

፳፪፤ ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡— እነሆ ፥ እጄን፡ ወደ፡ አሕዛብ፡ እነሣለሁ ፥ ዓላማዬንም፡ ወደ፡ ወገኖች፡ አቆማለሁ ፤ ወንዶች፡ ልጆችሽንም፡ በብብታቸው፡ ያመጡአቸዋል ፥ ሴቶች፡ ልጆችሽንም፡ በጫንቃቸው፡ ላይ፡

፳፫፤ ይሸከሙአቸዋል ። ነገሥታትም፡ አሳዳጊ፡ አባቶችሽ፡ ይሆናሉ ፥ እቴጌዎቻቸውም፡ ሞግዚቶችሽ፡ ይሆናሉ ፤ ግምባራቸውንም፡ ወደ፡ ምድር፡ ዝቅ፡ አድርገው፡ ይሰግዱልሻል ፥ የእግርሽንም፡ ትቢያ፡ ይልሳሉ ፤ እኔም፡ እግዚአብሔር፡ እንደ፡ ሆንሁ፡ ታውቂያለሽ ፥ እኔንም፡ በመተማመን፡ የሚጠባበቁ፡ አያፍሩም ።

፳፬፤ በውኑ፡ ብዝበዛ፡ ከኃያል፡ እጅ፡ ይወሰዳልን? ወይስ፡ የጨካኙ፡ ምርኮኞች፡ ያመልጣ

፳፭፤ ሉን? እግዚአብሔር፡ ግን፡ እንዲህ፡ ይላል፡— በኃያላን፡ የተማረኩ፡ ይወሰዳሉ ፥ የጨካኞችም፡ ብዝበዛ፡ ያመልጣል ፤ ከአንቺ፡ ጋር፡ የሚጣሉትን፡ እጣላቸዋለሁ ፥ ልጆችሽንም፡

፳፮፤ አድናለሁ ። አስጨናቂዎችሽንም፡ ሥጋቸውን፡ አስበላቸዋለሁ ፥ እንደ፡ ጣፋጭም፡ ወይን፡ ጠጅ፡ ደማቸውን፡ ጠጥተው፡ ይሰክራሉ ፤ ሥጋ፡ ለባሹም፡ ሁሉ፡ እኔ፡ እግዚአብሔር፡ መድኃኒትሽና፡ ታዳጊሽ ፥ የያዕቆብ፡ ኃያል፡ እንደ፡ ሆንሁ፡ ያውቃል ።

## ምዕራፍ፡ ፶ ።

፩፤ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡— እናታችሁን፡ የፈታሁበት፡ የፍችዋ፡ ጽሕፈት፡ የት፡ አለ? ወይስ፡ እናንተን፡ የሸጥሁ፡ ከአበዳሪዎች፡ ለየትኛው፡ ነው? እነሆ ፥ ስለ፡ ኃጢአታችሁ፡ ተሸጣችኋል ፥ ስለ፡ በደላችሁም፡

፪፤ እናታችሁ፡ ተፈትታለች ። በመጣሁስ፡ ጊዜ፡ ሰው፡ ስለ፡ ምን፡ አልነበረም? በጠራሁስ፡ ጊዜ፡ የሚመልስ፡ ስለ፡ ምን፡ አልነበረም? መታደግ፡ እንዳትችል፡ እጄ፡ አጭር፡ ሆናለችን? ወይስ፡ ለማዳን፡ ኃይል፡ የለኝምን? እነሆ ፥ በገሥጽሁ፡ ጊዜ፡ ባሕርን፡ አደርቃለሁ ፥ ወንዞችንም፡ ምድረ፡ በዳ፡ አደርጋቸዋለሁ ፤ ውኃም፡ በማጣት፡ ዓሦቻቸው፡ ይገማሉ፡ በጥማትም፡ ይሞ

፫፤ ታሉ ። ሰማያትን፡ ጥቍረት፡ አለብሳቸዋለሁ ፥ መጋረጃቸውንም፡ ማቅ፡ አደርጋለሁ ።

፬፤ የደከመውን፡ በቃል፡ እንዴት፡ እንደምደግፍ፡ አውቅ፡ ዘንድ፡ ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ የተማሩትን፡ ምላስ፡ ሰጥቶኛል ፤ ማለዳ፡ ማለዳ፡ ያነቃኛል ፥ እንደ፡ ተማሪዎችም፡ ትሰማ፡ ዘንድ፡

፭፡ ጆሮዬን ፡ ያነቃቃል ። ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡
ጆሮዬን ፡ ከፍቶአል ÷ እኔም ፡ ዓመፀኛ ፡ አልነ
በርሁም ፡ ወደ ፡ ኋላዬም ፡ አልተመለስሁም ።
፮፡ ጀርባዬን ፡ ለገራፊዎች ፡ ጕንጬንም ፡ ለጠጕር ፡
ነጪዎች ፡ ሰጠሁ ÷ ፊቴንም ፡ ከውርደትና ፡
፯፡ ከትፋት ፡ አልመለስሁም ። ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ይረዳኛልና ፡ ስለዚህ ፡ አልታወክሁም ፤
ስለዚህም ፡ ፊቴን ፡ እንደ ፡ ባልጩት ፡ ድንጋይ ፡
አድርጌዋለሁ ÷ እንዳላፍርም ፡ አውቃለሁ ።
፰፡ የሚያጸድቀኝ ፡ ቅርብ ፡ ነው ፤ ከእኔስ ፡ ጋር ፡
የሚከራከር ፡ ማን ፡ ነው ? በአንድነት ፡ እን
ቁም ፤ የሚከራከረኝ ፡ ማን ፡ ነው ? ወደ ፡ እኔ ፡
፱፡ ይቅረብ ። እነሆ ÷ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይረ
ዳኛል ፤ ማን ፡ ይፈርድብኛል ? እነሆ ÷ ሁሉ ፡
እንደ ፡ ልብስ ፡ ያረጃሉ ፡ ብልም ፡ ይበላቸዋል ።
፲፡ ከእናንተ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ÷ የባሪ
ያውንም ፡ ቃል ፡ የሚሰማ ÷ በጨለማም ፡ የሚ
ሄድ ÷ ብርሃንም ፡ የሌለው ÷ ነገር ፡ ግን ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ስም ፡ የሚታመን ÷ በአምላኩም ፡
፲፩፡ የሚደገፍ ፡ ማን ፡ ነው ? እነሆ ÷ እሳት ፡ የም
ታነድዱ ፡ የእሳትንም ፡ ወላፈን ፡ የምትታጠቁ ፡
ሁላችሁ ÷ በእሳታችሁ ፡ ነበልባል ፡ በነደዳች
ሁትም ፡ ወላፈን ፡ ሂዱ ፤ ይህ ፡ ከእጄ ፡ ይሆንባ
ችኋል ፤ በኀዘን ፡ ትተኛላችሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፶፩ ።

፩፡ እናንተ ፡ ጽድቅን ፡ የምትከተሉ ፡ እግዚአብ
ሔርንም ፡ የምትሹ ÷ ስሙኝ ፤ ከእርሱ ፡ የተቈ
ረጣችሁበትን ፡ ድንጋይ ፡ ከእርሱም ፡ የተቈፈ
፪፡ ራችሁበትን ፡ ጕድጓድ ፡ ተመልከቱ ። ወደ ፡
አባታችሁ ፡ ወደ ፡ አብርሃም ÷ ወደ ፡ ወለደቻ
ችሁም ፡ ወደ ፡ ሳራ ፡ ተመልከቱ ፤ አንድ ፡ ብቻ
ውን ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ጠራሁት ÷ ባረክሁትም ፡
፫፡ አበዛሁትም ። እግዚአብሔርም ፡ ጽዮንን ፡ ያጽ
ናናል ፤ በእርስዋም ፡ ባድማ ፡ የሆነውን ፡ ሁሉ ፡
ያጽናናል ÷ ምድረ ፡ በዳዋንም ፡ እንደ ፡ ዔድን ፡
በረሀዋንም ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ገነት ፡ ያደ
ርጋል ፤ ደስታና ፡ ተድላ ፡ ምስጋናና ፡ የዝማሬ ፡
ድምፅ ፡ ይገኝበታል ።
፬፡ ወገኔ ፡ ሆይ ÷ አድምጠኝ ፤ ሕዝቤ ፡ ሆይ ÷
ስማኝ ፤ ሕግ ፡ ከእኔ ፡ ይወጣልና ፡ ፍርዴም ፡ ለአ
፭፡ ሕዛብ ፡ ብርሃን ፡ ይሆናልና ። ጽድቄ ፡ ፈጥኖ ፡
ቀርቦአል ÷ ማዳኔም ፡ ወጥቶአል ÷ ክንዴም ፡
በአሕዛብ ፡ ላይ ፡ ይፈርዳል ፤ ደሴቶች ፡ እኔን ፡
በመተማመን ፡ ይጠባበቃሉ ÷ በክንዴም ፡ ይታ
፮፡ መናሉ ። ዓይናችሁን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አንሡ ÷
ወደ ፡ ታችም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ተመልከቱ ፤ ሰማ
ያት ፡ እንደ ፡ ጢስ ፡ በንነው ፡ ይጠፋሉ ÷ ምድ
ርም ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ታረጃለች ÷ የሚኖሩባ
ትም ፡ እንዲሁ ፡ ይሞታሉ ፤ ማዳኔ ፡ ግን ፡ ለዘላ
ለም ፡ ይሆናል ÷ ጽድቄም ፡ አይፈርስም ።
፯፡ ጽድቅን ፡ የምታውቁ ፡ ሕጌም ፡ በልባችሁ ፡
ያለ ፡ ሕዝብ ፡ ሆይ ÷ ስሙኝ ፤ የሰውን ፡ ተግዳ
ሮት ፡ አትፍሩ ÷ በስድባቸውም ፡ አትደንግጡ ።

፰፡ እንደ ፡ ልብስም ፡ ብል ፡ ይበላቸዋል ÷ እንደ ፡
በግ ፡ ጠጕርም ፡ ትል ፡ ይበላቸዋል ፤ ጽድቄ ፡
ግን ፡ ለዘላለም ፡ ማዳኔም ፡ ለትውልድ ፡ ሁሉ ፡
ይሆናል ።
፱፡ የእግዚአብሔር ፡ ክንድ ፡ ሆይ ÷ ተነሥ ÷
ተነሥ ÷ ኃይልንም ፡ ልበስ ፤ በቀድሞው ፡ ወራ
ትና ፡ በጥንቱ ፡ ዘመን ፡ በነበረው ፡ ትውልድ ፡
እንደ ፡ ሆነው ፡ ተነሥ ። ረዓብን ፡ የቈራረጥህ ፡ ዘን
፲፡ ዶውንም ፡ የወጋህ ፡ አንተ ፡ አይደለህምን ? ባሕ
ሩንና ፡ የታላቁን ፡ ጥልቅ ፡ ውኃ ፡ ያደረቅኸው ÷
የዳኑትም ፡ ይሻገሩ ፡ ዘንድ ፡ ጠሊቁን ፡ ባሕር ፡
መንገድ ፡ ያደረግህ ፡ አንተ ፡ አይደለህምን ?
፲፩፡ እግዚአብሔርም ፡ የተቤዣቸው ፡ ይመለሳሉ ፡
ወደ ፡ ጽዮንም ፡ ይመጣሉ ፤ የዘላለምም ፡ ደስታ ፡
በራሳቸው ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፤ ደስታንና ፡ ተድ
ላን ፡ ያገኛሉ ÷ ኀዘንና ፡ ልቅሶም ፡ ይሸሻል ።
፲፪፡ የማጽናናችሁ ፡ እኔ ፡ ነኝ ÷ እኔ ፡ ነኝ ፤ የሚሞተ
ውን ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሣርም ፡ የሚጠወልገውን ፡
የሰው ፡ ልጅ ፡ ትፈራ ፡ ዘንድ ፡ አንተ ፡ ማን ፡ ነህ ?
፲፫፡ ሰማያትንም ፡ የዘረጋውን ፡ ምድርንም ፡ የመሠ
ረተውን ፡ ፈጣሪህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ረስተ
ሃል ፤ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ ባዘጋጀ ፡ ጊዜ ፡ ከአስጨ
ናቂው ፡ ቍጣ ፡ የተነሣ ፡ ሁልጊዜ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡
ፈርተሃል ፤ የአስጨናቂው ፡ ቍጣ ፡ የት ፡ አለ ?
፲፬፡ ምርኮኛ ፡ ፈጥኖ ፡ ይፈታል ፤ አይሞትም ፡ ወደ ፡
ጕድጓድም ፡ አይወርድም ÷ እንጀራም ፡ አይጐ
፲፭፡ ድልበትም ። ሞገዱም ፡ እንዲተምም ፡ ባሕርን ፡
የማናውጥ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እኔ ፡
ነኝ ÷ ስሜም ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡
፲፮፡ ነው ። ሰማያትን ፡ እዘረጋ ፡ ዘንድ ፡ ምድርንም ፡
እመሠርት ፡ ዘንድ ÷ ጽዮንንም ፡— አንቺ ፡ ሕዝቤ ፡
ነሽ ፡ እል ፡ ዘንድ ፡ ቃሌን ፡ በአፍህ ፡ አድርጌአ
ለሁ ÷ በእጄም ፡ ጥላ ፡ ጋርጄሃለሁ ።
፲፯፡ ከእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ የቍጣውን ፡ ጽዋ ፡ የጠ
ጣሽ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ÷ ንቂ ÷ ንቂ ÷ ቁሚ ፤
የሚያንገደግድን ፡ ዋንጫ ፡ ጠጥተሻል ፡ ጨልጠ
፲፰፡ ሽውማል ። ከወለደቻቸው ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ የሚ
መራት ፡ የለም ÷ ከሳደገቻቸውም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡
፲፱፡ እጅዋን ፡ የሚይዝ ፡ የለም ። እነዚህ ፡ ሁለት ፡
ነገሮች ፡ ሆነውብሻል ÷ ማንስ ፡ ያስተዛዝንሻል ?
መፈታትና ፡ ጥፋት ፡ ራብና ፡ ሰይፍ ፡ ናቸው ፤ እን
፳፡ ዴትስ ፡ አድርጌ ፡ አጽናናሻለሁ ? ልጆችሽ ፡ ዝለ
ዋል ፤ በወጥመድ ፡ እንደ ፡ ተያዘ ፡ ሚዳቋ ፡ በአ
ደባባይ ፡ ሁሉ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ተኝተዋል ፤ በእግ
ዚአብሔር ፡ ቍጣና ፡ በአምላክሽ ፡ ተግሣጽ ፡
ተሞልተዋል ።
፳፩፡ ስለዚህም ፡ ያለ ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡ የሰከርሽ ፡
፳፪፡ አንቺ ፡ ችግረኛ ÷ ይህን ፡ ስሚ ፤ ስለ ፡ ወገኑ ፡
የሚምዋገት ፡ አምላክሽ ፡ ጌታሽ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ የሚያንገደ
ግድን ፡ ጽዋ ፡ የቍጣዬንም ፡ ዋንጫ ፡ ከእጅሽ ፡
ወስጃለሁ ፤ ደግመሽም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
፳፫፡ አትጠጪውም ። ነፍስሽንም ፡— እንሻገር ፡
ዘንድ ፡ ዝቅ ፡ በዪ ፡ በሚሉአት ፡ በአስጨናቂዎ

ችሽ ፡ እጅ ፡ አኖረዋለሁ ፤ ጀርባሽንም ፡ ለሚሻገሩት ፡ እንደ ፡ መሬትና ፡ እንደ ፡ መንገድ ፡ አደረግሽላቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፶፪ ።

፩፤ ጽዮን ፡ ሆይ ÷ ተነሺ ÷ ተነሺ ÷ ኃይልሽን ፡ ልበሺ ፤ ቅድስቲቱ ፡ ከተማ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ÷ ያልተገረዘና ፡ ርኩስ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አይገባብሽምና ፡ ጌጠኛ ፡ ልብስሽን ፡ ልበሺ ።
፪፤ ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ÷ ትቢያን ፡ አራግፊ ፤ ተነሺ ÷ ተቀመጪ ፤ ምርኮኛይቱ ፡ የጽዮን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ የአንገትሽን ፡ እስራት ፡ ፍቺ ።
፫፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በከንቱ ፡ ተሸጣችሁ ፡ ነበር ÷ ያለ ፡ ገንዘብም ፡ ትቤዠላ
፬፤ ችሁ ። ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ወገኔ ፡ በዚያ ፡ እንግዳ ፡ ሆኖ ፡ ይቀመጥ ፡ ዘንድ ፡ አስቀድሞ ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ወረደ ÷ አሦርም ፡
፭፤ ያለ ፡ ምክንያት ፡ በደለው ። ወገኔ ፡ በከንቱ ፡ ተወስዶአልና ፡ አሁን ፡ ከዚህ ፡ ምን ፡ አለኝ ? ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ የሚገዙአቸው ፡ ይጮኻሉ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ÷ ስሜም ፡ ሁል
፮፤ ጊዜ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ይሰደባል ። ስለዚህ ፡ ወገኔ ፡ ስሜን ፡ ያውቃል ÷ ስለዚህም ፡ የምናገር ፡ እኔ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ያውቃሉ ፤ እነሆ ÷ እኔ ፡ ነኝ ።
፯፤ የምስራች ፡ የሚናገር ÷ ሰላምንም ፡ የሚያወራ ÷ የመልካምንም ፡ ወሬ ፡ የምስራች ፡ የሚናገር ÷ መድኃኒትንም ፡ የሚያወራ ÷ ጽዮንንም ፡— አምላክሽ ፡ ነግሦአል ፡ የሚል ፡ ሰው ፡ እግሩ ፡ በተራሮች ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡ ያማረ ፡ ነው ።
፰፤ እነሆ ÷ ጕበኞችሽ ፡ ጮኸዋል ፤ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ጽዮን ፡ በተመለሰ ፡ ጊዜ ፡ ዓይን ፡ በዓይን ፡ ይተያያሉና ፡ ድምፃቸውን ፡ ያነሣሉ ÷ በአን
፱፤ ድነትም ፡ ይዘምራሉ ። እናንተ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ፍርስራሾች ፡ ሆይ ÷ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ አጽናንቶአልና ÷ ኢየሩሳሌምንም ፡ ታድጎአልና ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ÷ በአንድነትም ፡ ዘምሩ ።
፲፤ እግዚአብሔር ፡ የተቀደሰውን ፡ ክንዱን ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ገልጦአል ÷ በምድር ፡ ዳርቻ ፡ የሚኖሩትም ፡ ሁሉ ፡ የአምላካችንን ፡ መድኃኒት ፡ ያያሉ ።
፲፩፤ እናንተ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ዕቃ ፡ የምትሸከሙ ፡ ሆይ ÷ እልፍ ፡ በሉ ÷ እልፍ ፡ በሉ ÷ ከዚያ ፡ ውጡ ÷ ርኩስን ፡ ነገር ፡ አትንኩ ÷ ከመካከልዋ ፡
፲፪፤ ውጡ ÷ ንጹሐን ፡ ሁኑ ። እግዚአብሔር ፡ ይቀድማችኋልና ÷ የእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ ይከተላችኋልና ፡ በችኰላ ፡ አትወጡም ፡ በመኰብለልም ፡ አትሄዱም ።
፲፫፤ እነሆ ÷ ብሪያዬ ፡ በማስተዋል ፡ ያደርጋል ፤ ይከብራል ፡ ከፍ ፡ ከፍም ፡ ይላል ÷ እጅግ ፡ ታላ
፲፬፤ ቅም ፡ ይሆናል ። ፊቱ ፡ ከሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ÷ መልኩም ፡ ከሰዎች ፡ ልጆች ፡ ይልቅ ፡ ተጐሳቍሎአልና ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ እንደ ፡ ተደነቁ ÷ እንዲሁ ፡ ብዙ ፡ አሕዛብን ፡
፲፭፤ ያስደንቃል ፤ ያልተነገረላቸውንም ፡ ያያሉና ÷ ያልሰሙትንም ፡ ያስተውላሉና ፡ ነገሥታት ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ አፋቸውን ፡ ይዘጋሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፶፫ ።

፩፤ የሰማነውን ፡ ነገር ፡ ማን ፡ አምኖአል ? የእግዚአብሔርስ ፡ ክንድ ፡ ለማን ፡ ተገልጦአል ?
፪፤ በፊቱ ፡ እንደ ፡ ቡቃያ ፡ ከደረቅም ፡ መሬት ፡ እንደ ፡ ሥር ፡ አደገ ፤ መልክና ፡ ውበት ፡ የለውም ÷ ባየነውም ፡ ጊዜ ፡ እንወድደው ፡
፫፤ ዘንድ ፡ ደም ፡ ግባት ፡ የለውም ። የተናቀ ፡ ከሰውም ፡ የተጠላ ÷ የሕማም ፡ ሰው ፡ ደዌንም ፡ የሚያውቅ ፡ ነው ፤ ሰውም ፡ ፊቱን ፡ እንደሚሰውርበት ፡ የተናቀ ፡ ነው ÷ እኛም ፡ አላከበርነውም ።
፬፤ በእውነት ፡ ደዌያችንን ፡ ተቀበለ ፡ ሕመማችንንም ፡ ተሸከሞአል ፤ እኛ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ተመታ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተቀሠፈ ፡ እንደ ፡
፭፤ ተቸገረም ፡ ቈጠርነው ። እርሱ ፡ ግን ፡ ስለ ፡ መተላለፋችን ፡ ቈሰለ ÷ ስለ ፡ በደላችንም ፡ ደቀቀ ፤ የደኅንነታችንም ፡ ተግሣጽ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ነበረ ÷ በእርሱም ፡ ቍስል ፡ እኛ ፡ ተፈ
፮፤ ወስን ። እኛ ፡ ሁላችን ፡ እንደ ፡ በጎች ፡ ተቅበዘበዝን ፡ ጠፋን ፤ ከእኛ ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ገዛ ፡ መንገዱ ፡ አዘነበለ ፤ እግዚአብሔርም ፡ የሁላችንን ፡ በደል ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ አኖረ ።
፯፤ ተጨነቀ ፡ ተሣቀየም ፡ አፉንም ፡ አልከፈተም ፤ ለመታረድ ፡ እንደሚነዳ ፡ ጠቦት ÷ በሸላቶቹም ፡ ፊት ፡ ዝም ፡ እንደሚል ፡ በግ ÷ እንዲሁ ፡ አፉን ፡
፰፤ አልከፈተም ። በማስጨነቅና ፡ በፍርድ ፡ ተወሰደ ፤ ስለ ፡ ሕዝቤ ፡ ኃጢአት ፡ ተመትቶ ፡ ከሕያዋን ፡ ምድር ፡ እንደ ፡ ተወገደ ፡ ከትውልዱ ፡ ማን ፡
፱፤ አስተዋለ ? ከክፉዎችም ፡ ጋር ፡ መቃብሩን ፡ አደረጉ ÷ ከባለጠጎችም ፡ ጋር ፡ በሞቱ ፤ ሆኖም ፡ ግፍን ፡ አላደረገም ፡ ነበር ÷ በአፉም ፡ ተንኰል ፡ አልተገኘበትም ፡ ነበር ።
፲፤ እግዚአብሔርም ፡ በደዌ ፡ ያደቅቀው ፡ ዘንድ ፡ ፈቀደ ፤ ነፍሱን ፡ ስለ ፡ ኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ካደረገ ፡ በኋላ ዘሩን ፡ ያያል ÷ ዕድሜውም ፡ ይረዝማል ÷ የእግዚአብሔርም ፡ ፈቃድ ፡ በእጁ ፡
፲፩፤ ይከናወናል ። ከነፍሱ ፡ ድካም ፡ ብርሃን ፡ ያያል ፡ ደስም ፡ ይለዋል ፤ ጻድቅ ፡ ባሪያዬም ፡ በእውቀቱ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ ያጸድቃል ÷ ኃጢአታቸ
፲፪፤ ውንም ፡ ይሸከማል ። ስለዚህም ፡ እርሱ ፡ ብዙዎችን ፡ ይወርሳል ÷ ከኃያላንም ፡ ጋር ፡ ምርኮን ፡ ይከፋፈላል ፤ ነፍሱን ፡ ለሞት ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቶአልና ÷ ከዓመፀኞችም ፡ ጋር ፡ ተቈጥሮአልና ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ የብዙ ፡ ሰዎችን ፡ ኃጢአት ፡ ተሸከመ ÷ ስለ ፡ ዓመፀኞችም ፡ ማለደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፶፬ ።

፩፤ አንቺ ፡ ያልወለድሽ ፡ መካን ፡ ሆይ ÷ ዘምሪ ፤ አንቺ ፡ ያላማጥሽ ፡ ሆይ ÷ እልል ፡ በዪ ÷ ጩኺም ፤ ባል ፡ ካላት ፡ ይልቅ ፡ ፊት ፡ የሆነቺቱ ፡ ልጆች ፡ በዝተዋልና ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። የድን
፪፤

ኳንሽን፡ስፍራ፡አስፊ፣መጋረጃዎችሽንም፡
ይዘርጉ፤ አትቈጥቢ፤ አውታሮችሽን፡አስረ
፫፤ ዝሚ፡ካስሞችሽንም፡አጽኚ። በቀኝና፡በግራ፡
ትሰፋፊያለሽና፣ዘርሽም፡አሕዛብን፡ይወርሳ
ልና፣የፈረሱትንም፡ከተሞች፡መኖሪያ፡ያደ
ርጋልና።
፬፤ አታፍሪምና፡አትፍሪ፤አትዋረጂምና፡አት
ደንግጪ፤የሕፃንነትሽንም፡እፍረት፡ትረሺዋ
ለሽ፣የመበለትነትሽንም፡ስድብ፡ከእንግዲህ፡
፭፤ ወዲህ፡አታስቢም። ፈጣሪሽ፡ባልሽ፡ነው፣
ስሙም፡የሠራዊት፡ጌታ፡እግዚአብሔር፡
ነው፤የእስራኤልም፡ቅዱስ፡ታዳጊሽ፡ነው፣
እርሱም፡የምድር፡ሁሉ፡አምላክ፡ይባላል።
፮፤ እግዚአብሔር፡እንደ፡ተተወችና፡እንደ፡ተበ
ሳጨች፡በልጅነትዋም፡እንደ፡ተጣለች፡
፯፤ ሚስት፡ጠርቶሻል፣ይላል፡አምላክሽ። ጥቂት፡
ጊዜ፡ተውሁሽ፣በታላቅም፡ምሕረት፡እሰበ
፰፤ ስብሻለሁ። በጥቂት፡ቍጣ፡ለቅጽበት፡ዓይን፡
ፊቴን፡ከአንቺ፡ሰወርሁ፣በዘላለምም፡ቸር
ነት፡እምርሻለሁ፣ይላል፡ታዳጊሽ፡እግዚአ
፱፤ ብሔር። ይህ፡ለእኔ፡እንደ፡ኖኅ፡ውኃ፡ነው፤
የኖኅ፡ውኃ፡ደግሞ፡በምድር፡ላይ፡እንዳያ
ልፍ፡እንደ፡ማልሁ፣እንዲሁ፡አንቺን፡እን
፲፤ ዳልቈጣ፡እንዳልዘልፍሽም፡ምያለሁ። ተራ
ሮች፡ይፈልሳሉ፣ኮረብቶችም፡ይወገዳሉ፤
ቸርነቴ፡ግን፡ከአንቺ፡ዘንድ፡አይፈልስም፡
የሰላሜም፡ቃል፡ኪዳን፡አይወገድም፣ይላል፡
መሐሪሽ፡እግዚአብሔር።
፲፩፤ አንቺ፡የተቸገርሽ፡በዐውሎ፡ነፋስም፡የተ
ናወጥሽ፡ያልተጽናናሽም፣እነሆ፣ድንጋዮች
ሽን፡ሸላልሜ፡እገነባለሁ፣በሰንፔርም፡እመ
፲፪፤ ሠርትሻለሁ። የግንብሽንም፡ጕልላት፡በቀይ፡
ዕንቍ፣በሮችሽንም፡በሚያብረቀርቅ፡ዕንቍ፣
ዳርቻሽንም፡ሁሉ፡በከበሩ፡ድንጋዮች፡እሠ
፲፫፤ ራለሁ። ልጆችሽም፡ሁሉ፡ከእግዚአብሔር፡
የተማሩ፡ይሆናሉ፣የልጆችሽም፡ሰላም፡ብዙ፡
፲፬፤ ይሆናል። በጽድቅ፡ትታነጺያለሽ፤ ከግፍ፡
ራቂ፣አትፈሪምም፣ድንጋጤም፡ወደ፡አንቺ፡
፲፭፤ አትቀርብም። እነሆ፣ይሰበሰባሉ፣ነገር፡ግን፡
ከእኔ፡ዘንድ፡አይሆንም፤ በአንቺም፡ላይ፡
የሚሰበሰቡ፡ሁሉ፡ከአንቺ፡የተነሣ፡ይወድ
፲፮፤ ቃሉ። እነሆ፣ፍሙን፡በወናፍ፡የሚያናፋ፡
ለሥራውም፡መሣሪያ፡የሚያወጣ፡ብረት፡
ሠሪን፡እኔ፡ፈጥሬአለሁ፤የሚያፈርሰውንም፡
፲፯፤ እንዲያጠፋ፡ፈጥሬአለሁ። በአንቺ፡ላይ፡የተ
ሠራ፡መሣሪያ፡ሁሉ፡አይከናወንም፤ በፍር
ድም፡በሚነሣብሽ፡ምላስ፡ሁሉ፡ትፈርጂበ
ታለሽ። የእግዚአብሔር፡ባሪያዎች፡ርስት፡
ይህ፡ነው፣ጽድቃቸውም፡ከእኔ፡ዘንድ፡ነው፣
ይላል፡እግዚአብሔር።

## ምዕራፍ፡ ፶፭።

፩፤ እናንተ፡የተጠማችሁ፡ሁሉ፣ወደ፡ውኃ፡
ኑ፣ገንዘብም፡የሌላችሁ፡ኑና፡ግዙ፡ብሉም፤
ኑ፡ያለ፡ገንዘብም፡ያለ፡ዋጋም፡የወይን፡
፪፤ ጠጅና፡ወተት፡ግዙ። ገንዘብን፡እንጀራ፡
ላይደለ፣የድካማችሁንም፡ዋጋ፡ለማያጠ
ግብ፡ነገር፡ለምን፡ትመዝናላችሁ? አድም
ጡኝ፣በረከትንም፡ብሉ፣ሰውነታችሁም፡
፫፤ በጮማ፡ደስ፡ይበለው። ጆሮአችሁን፡አዘን
ብሉ፡ወደ፡እኔም፡ቅረቡ፤ስሙ፡ሰውነታች
ሁም፡በሕይወት፡ትኖራለች፤የታመነችይቱን፡
የዳዊትን፡ምሕረት፣የዘላለምን፡ቃል፡ኪዳን፡
፬፤ ከእናንተ፡ጋር፡አደርጋለሁ። እነሆ፣ለአሕ
ዛብ፡ምስክር፣ለወገኖችም፡አለቃና፡አዛዥ፡
፭፤ እንዲሆን፡ሰጥቼዋለሁ። እነሆ፣የማታውቀ
ውን፡ሕዝብ፡ትጠራለህ፣የእስራኤልም፡
ቅዱስ፡አክብሮሃልና፡ስለ፡አምላክህ፡ስለ፡
እግዚአብሔር፡የማያውቁህ፡ሕዝብ፡ወደ፡
አንተ፡ይሮጣሉ።
፮፤ እግዚአብሔር፡በሚገኝበት፡ጊዜ፡ፈል
፯፤ ጉት፣ቀርቦም፡ሳለ፡ጥሩት፤ ክፉ፡ሰው፡
መንገዱን፡በደለኛም፡አሳቡን፡ይተው፤
ወደ፡እግዚአብሔርም፡ይመለስ፡እርሱም፡
ይምረዋል፣ይቅርታውም፡ብዙ፡ነውና፡
፰፤ ወደ፡አምላካችን፡ይመለስ። አሳቤ፡እንደ፡
አሳባችሁ፡መንገዳችሁም፡እንደ፡መንገዴ፡
፱፤ አይደለምና፣ይላል፡እግዚአብሔር። ሰማይ፡
ከምድር፡ከፍ፡እንደሚል፣እንዲሁ፡መን
ገዴ፡ከመንገዳችሁ፡አሳቤም፡ከአሳባችሁ፡
፲፤ ከፍ፡ያለ፡ነው። ዝናብና፡በረዶ፡ከሰማይ፡
እንደሚወርድ፣ምድርን፡እንደሚያረካት፣
ታበቅልና፡ታፈራም፡ዘንድ፡እንደሚያደር
ጋት፣ዘርንም፡ለሚዘራ፡እንጀራንም፡ለሚ
በላ፡እንደሚሰጥ፡እንጂ፡ወደ፡ሰማይ፡እንደ
፲፩፤ ማይመለስ፣ከአፌ፡የሚወጣ፡ቃሌ፡እንዲሁ፡
ይሆናል፤ የምሻውን፡ያደርጋል፡የላክሁት
ንም፡ይፈጽማል፡እንጂ፡ወደ፡እኔ፡በከንቱ፡
፲፪፤ አይመለስም። እናንተም፡በደስታ፡ትወጣላ
ችሁ፡በሰላምም፡ትሸኛላችሁ፤ ተራሮችና፡
ኮረብቶች፡በፊታችሁ፡እልልታ፡ያደርጋሉ፣
፲፫፤ የሜዳም፡ዛፎች፡ሁሉ፡ያጨበጭባሉ። በእ
ሾህም፡ፋንታ፡ጥድ፡በኵርንችትም፡ፋንታ፡
ባርሰነት፡ይበቅላል፤ለእግዚአብሔርም፡መታ
ሰቢያና፡ለዘላለምም፡የማይጠፋ፡ምልክት፡
ይሆናል።

## ምዕራፍ፡ ፶፮።

፩፤ እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፤— ማዳኔ፡
ሊመጣ፡ጽድቄም፡ሊገለጥ፡ቀርቦአልና፡ፍር
፪፤ ድን፡ጠብቁ፡ጽድቅንም፡አድርጉ። ይህን፡
የሚያደርግ፡ሰው፡ይህንንም፡የሚይዝ፡የሰው፡
ልጅ፣እንዳያረክሰው፡ሰንበትንም፡የሚጠ
ብቅ፡እጁንም፡ክፉት፡ከማድረግ፡የሚጠ
፫፤ ብቅ፡ብፁዕ፡ነው። ወደ፡እግዚአብሔርም፡የተ
ጠጋ፡መጻተኛ፤— በእውነት፡እግዚአብሔር፡
ከሕዝቡ፡ይለየኛል፡አይበል! ጃንደረባም፤—
፬፤ እነሆ፣እኔ፡ደረቅ፡ዛፍ፡ነኝ፡አይበል። እግ

ዚአብሔር ፡ ሰንበቴን ፡ ስለሚጠብቁ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘኝንም ፡ ነገር ፡ ስለሚመርጡ ፡ ቃል ፡ ኪዳኔንም ፡ ስለሚይዙ ፡ ጃንደረቦች ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— ፭ በቤቴና ፡ በቅጥሬ ፡ ውስጥ ፡ ከወንዶችና ፡ ከሴቶች ፡ ልጆች ፡ ይልቅ ፡ የሚበልጥ ፡ መታሰቢያና ፡ ስም ፡ እሰጣቸዋለሁ ፤ የማይጠፋም ፡ የዘላለም ፡ ስም ፡ እሰጣቸዋለሁ ። ፮ ያገለግሉት ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ ይወድዱ ፡ ዘንድ ፡ በሪያዎቹም ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚጠጉትንም ፡ መጻተኞች ÷ እንዳያረክሱት ፡ ሰንበትን ፡ የሚጠብቁትን ፡ ፯ ቃል ፡ ኪዳኔንም ፡ የሚይዙትን ፡ ሁሉ ÷ ወደ ፡ ተቀደሰ ፡ ተራራዬ ፡ አመጣቸዋለሁ ÷ በጸሎቴም ፡ ቤት ፡ ደስ ፡ አሰኛቸዋለሁ ፤ ቤቴ ፡ ለአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ የሚሆን ፡ የጸሎት ፡ ቤት ፡ ይባላልና ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕታቸውንና ፡ ሌላ ፡ መሥዋዕታቸውን ፡ በመሠዊያዬ ፡ ላይ ፡ እቀበላለሁ ። ፰ ከእስራኤል ፡ የተበተኑትን ፡ የሚሰበስብ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡— ወደ ፡ ተሰበሰቡት ፡ ዘንድ ፡ ሌሎችን ፡ እሰበስብለታለሁ ፡ ይላል ።

፱ እናንተ ፡ የምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ÷ እናንተም ፡ የዱር ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ÷ ትበሉ ፡ ዘንድ ፡ ቅረቡ ። ፲ ጉበኞቹ ፡ ዕውሮች ፡ ናቸው ÷ ሁሉ ፡ ያለ ፡ እውቀት ፡ ናቸው ፤ ሁሉም ፡ ዲዳ ፡ የሆኑ ፡ ውሾች ፡ ናቸው ፡ ይጮኹም ፡ ዘንድ ፡ አይችሉም ፤ ሕልምን ፡ ያልማሉ ፤ ይተኛሉ ፤ ማንቀላፋትንም ፡ ይወድዳሉ ። ፲፩ መብል ፡ ወዳጆች ፡ ከቶ ፡ የማይጠግቡ ፡ ውሾች ፡ ናቸው ÷ እነርሱም ፡ ያስተውሉ ፡ ዘንድ ፡ የማይችሉ ፡ እረኞች ፡ ናቸው ፤ ሁሉ ፡ ወደ ፡ መንገዳቸው ÷ ከፊተኛው ፡ እስከ ፡ ኋለኛው ፡ ድረስ ፡ ሁሉ ÷ እያንዳንዳቸው ፡ ወደ ፡ ጥቅማቸው ፡ ዘወር ፡ ብለዋል ። ፲፪ ኑ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ እንውሰድ ÷ በሚያሰክርም ፡ መጠጥ ፡ እንርከ ፤ ዛሬም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንዲሁ ፡ ነገ ፡ ይሆናል ÷ ከዛሬም ፡ ይልቅ ፡ እጅግ ፡ ይበልጣል ፡ ይላሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፶፯ ።

፩ ጻድቅ ፡ ይሞታል ÷ በልቡም ፡ ነገሩን ፡ የሚያኖር ፡ የለም ፤ ምሕረተኞችም ፡ ይወገዳሉ ÷ ጻድቅም ፡ ከክፉት ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ተወገደ ፡ ፪ ማንም ፡ አያስተውልም ። ወደ ፡ ሰላም ፡ ይገባል ፤ በቅንነት ፡ የሄደ ፡ በአልጋው ፡ ላይ ፡ ያርፋል ።

፫ እናንተ ፡ የአስማተኛይቱ ፡ ልጆች ÷ የአመንዝራውና ፡ የጋለሞታይቱ ፡ ዘር ÷ ወደዚህ ፡ ፬ ቅረቡ ። በማን ፡ ታላግጣላችሁ ? በማንስ ፡ ላይ ፡ አፋችሁን ፡ ታላቅቃላችሁ ? ምላሳችሁንስ ፡ ፭ በማን ፡ ላይ ፡ ታስረዝማላችሁ ? እናንተ ፡ በአድባር ፡ ዛፎች ፡ መካከል ፡ በለመለመም ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ በታች ፡ በፍትወት ፡ የምትቃጠሉ ÷ እናንተም ፡ በሸለቆች ፡ ውስጥ ፡ በዓለትም ፡ ስንጣቂዎች ፡ በታች ፡ ሕፃናትን ፡ የምታርዱ ÷ የዓመፅ ፡ ልጆችና ፡ የሐሰት ፡ ዘር ፡ አይደላችሁ ምን ? ፮ በሸለቆው ፡ ውስጥ ፡ ያሉ ፡ የለዘቡ ፡ ድንጋዮች ፡ እድል ፡ ፈንታሽ ፡ ናቸው ÷ እነርሱም ፡ ዕጣሽ ፡ ናቸው ፤ ለእነርሱም ፡ የመጠጥ ፡ ቍርባን ፡ አፍስሰሻል ÷ የእህልንም ፡ ቍርባን ፡ አቅርበሻል ። እንግዲህ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ አልቈጣምን ? ፯ ከፍ ፡ ባለውም ፡ በረዘመውም ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ መኝታሽን ፡ አደረግሽ ÷ መሥዋዕትንም ፡ ትሠዊ ፡ ዘንድ ፡ ወደዚያ ፡ ወጣሽ ። ፰ ከመዝጊያውና ፡ ከመቃኑ ፡ በኋላ ፡ መታሰቢያሽን ፡ አደረግሽ ፤ እኔን ፡ ትተሽ ፡ ለሌላ ፡ ተገልጠሻል ÷ ወጥተሽ ፡ መኝታሽን ፡ አስፍተሻል ፤ ቃል ፡ ኪዳንም ፡ ተጋብተሻቸው ÷ ባየሽበትም ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ መኝታቸውን ፡ ወደድሽ ። ፱ ዘይትም ፡ ይዘሽ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ሄድሽ ÷ ሽቱሽንም ፡ አበዛሽ ÷ መልእክተኞችሽንም ፡ ወደ ፡ ሩቅ ፡ ላክሽ ÷ እስከ ፡ ሲኦልም ፡ ድረስ ፡ ተዋረድሽ ። ፲ በመንገድሽም ፡ ብዛት ፡ ደከምሽ ÷ ነገር ፡ ግን ፡— ተስፋ ፡ የለም ፡ አላልሽም ፤ የጕልበትን ፡ መታደስ ፡ አገኘሽ ÷ ስለዚህም ፡ አልዛልሽም ።

፲፩ ሐሰትን ፡ የተናገርሺው ፡ እኔንም ፡ ያላሰብሺው ፡ በልብሽም ፡ ነገሩን ፡ ያላኖርሺው ፡ ማንን ፡ ሰግተሽ ፡ ነው ? ማንንስ ፡ ፈርተሽ ፡ ነው ? እኔ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ዝም ፡ እልሁ ÷ አንቺም ፡ አልፈራሽም ። ፲፪ እኔ ፡ ጽድቅሽን ፡ እናገራለሁ ÷ ሥራሽም ፡ አይረባሽም ። ፲፫ ወደ ፡ አንቺ ፡ የሰበሰብሻቸው ፡ በጮኽሽ ፡ ጊዜ ፡ ይታደጉሽ ፤ ነፋስ ፡ ግን ፡ ይወስዳቸዋል ፡ ሽውሽውታም ፡ ሁሉን ፡ ያስወግዳቸዋል ። በእኔ ፡ የታመነ ፡ ግን ፡ ምድሪቱን ፡ ይገዛል ÷ የተቀደሰውንም ፡ ተራራዬን ፡ ይወርሳል ።

፲፬ እርሱም ፡— ጥረጉ ÷ መንገድን ፡ አዘጋጁ ÷ ከሕዝቤም ፡ መንገድ ፡ ዕንቅፋትን ፡ አውጡ ፡ ይላል ። ፲፭ ለዘላለም ፡ የሚኖር ፡ ስሙም ፡ ቅዱስ ፡ የሆነ ÷ ከፍ ፡ ያለው ፡ ልዑል ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የተዋረዱትን ፡ ሰዎች ፡ መንፈስ ፡ ሕያው ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ÷ የተቀጠቀጠውንም ፡ ልብ ፡ ሕያው ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ÷ የተቀጠቀጠና ፡ የተዋረደ ፡ መንፈስ ፡ ካለው ፡ ጋር ፡ በከፍታና ፡ በተቀደሰ ፡ ስፍራ ፡ እቀመጣለሁ ። ፲፮ መንፈስም ፡ የፈጠርሁትም ፡ ነፍስ ፡ ከፊቴ ፡ እንዳይዝል ፡ ለዘላለም ፡ አልጣላም ÷ ሁልጊዜም ፡ አልቈጣም ። ፲፯ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ ጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ተቈጥቼ ፡ቀሠፍሁት ÷ ፊቴን ፡ሰውሬ ፡ ተቈጣሁ ፤ እርሱም ፡ በልቡ ፡ መንገድ ፡ እያፈገፈገ ፡ ሄደ ። ፲፰ መንገዱን ፡ አይቻለሁ ፡ እፈውሰውማለሁ ÷ እመራውማለሁ ÷ ለእርሱና ፡ ስለ ፡ እርሱም ፡ ለሚያለቅሱ ፡ መጽናናትን ፡ እመልሳለሁ ። ፲፱ የከንፈሮችን ፡ ፍሬ ፡ እፈጥራለሁ ፤ በሩቅም ፡ በቅርብም ፡ ላለው ፡ ሰላም ፡ ሰላም ፡ ይሁን ÷ እፈውሰውማለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፳ ክፉዎች ፡ ግን ፡ እንደሚንቀሳቀስ ፡ ባሕር ፡ ናቸው ፤ ጸጥ ፡ ይል ፡ ዘንድ ፡ አይችልምና ÷ ውኆቹም ፡ ጭቃና ፡ ጕድፍ ፡ ያወጣሉና ። ፳፩ ለክፉዎች ፡ ሰላም ፡ የላቸውም ፡ ይላል ፡ አምላኬ ።

## ምዕራፍ ፡ ፶፰ ።

፩ በኃይልህ ፡ ጩኽ ፥ አትቈጥብ ፥ ድምፅህን ፡ እንደ ፡ መለከት ፡ አንሣ ፥ ለሕዝቤ ፡ መተላለፋቸውን ፡ ለያዕቆብ ፡ ቤትም ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ንገር ። ፪ ነገር ፡ ግን ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ይሹኛል ፡ መንገዴንም ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ ይወድዳሉ ፤ ጽድቅን ፡ እንዳደረጉ ፡ የአምላካቸውንም ፡ ፍርድ ፡ እንዳልተዉ ፡ ሕዝብ ፡ እውነተኛውን ፡ ፍርድ ፡ ይለምኑኛል ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ለመቅረብ ፡ ይወድዳሉ ። ፫ ስለ ፡ ምን ፡ ጾምን ፥ አንተም ፡ አልተመለከትኸንም ? ሰውነታችንንስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አዋረድን ፥ አንተም ፡ አላወቅህም ? ይላሉ ። እነሆ ፥ በጾማችሁ ፡ ቀን ፡ ፈቃዳችሁን ፡ ታደርጋላችሁ ፥ ሠራተኞቻችሁንም ፡ ሁሉ ፡ ታስጨንቃላችሁ ። ፬ እነሆ ፥ ለጥልና ፡ ለክርክር ፡ ትጾማላችሁ ፡ በግፍ ፡ ጡጫም ፡ ትማታላችሁ ፤ ድምፃችሁንም ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ታሰሙ ፡ ዘንድ ፡ ዛሬ ፡ እንደምትጾሙት ፡ አትጾሙም ። ፭ እኔ ፡ የመረጥሁት ፡ ጾም ፡ ይህ ፡ ነውን ? ሰውስ ፡ ነፍሱን ፡ የሚያዋርድበት ፡ እንደዚህ ፡ ባለ ፡ ቀን ፡ ነውን ? በውኑ ፡ ራሱን ፡ እንደ ፡ እንግጫ ፡ ዝቅ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ማቅንና ፡ አመድንም ፡ በበታቹ ፡ ያነጥፍ ፡ ዘንድ ፡ ነውን ? በውኑ ፡ ይህን ፡ ጾም ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ዘንድ ፡ የተወደደ ፡ ቀን ፡ ትለዋለህን ? ፮ እኔስ ፡ የመረጥሁት ፡ ጾም ፡ ይህ ፡ አይደለምን ? የበደልን ፡ እስራት ፡ ትፈቱ ፡ ዘንድ ፥ የቀንበርንስ ፡ ጠፍር ፡ ትለቅቁ ፡ ዘንድ ፥ የተገፉትንስ ፡ አርነት ፡ ትሰድዱ ፡ ዘንድ ፥ ቀንበሩንስ ፡ ሁሉ ፡ ትሰብሩ ፡ ዘንድ ፡ አይደለምን ? ፯ እንጀራህንስ ፡ ለተራበ ፡ ትቈርስ ፡ ዘንድ ፥ ስደተኞቹን ፡ ድሆች ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ ታገባ ፡ ዘንድ ፥ የተራቈተውንስ ፡ ብታይ ፡ ታለብሰው ፡ ዘንድ ፥ ከሥጋ ፡ ዘመድህ ፡ እንዳትሸሸግ ፡ አይደለምን ? ፰ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ብርሃንህ ፡ እንደ ፡ ንጋት ፡ ይበራል ፥ ፈውስህም ፡ ፈጥኖ ፡ ይበቅላል ፥ ጽድቅህም ፡ በፊትህ ፡ ይሄዳል ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ በኋላህ ፡ ሆኖ ፡ ይጠብቅሃል ። ፱ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ትጠራለህ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ይሰማሃል ፤ ትጮኻለህ ፡ እርሱም ፦ እነሆኝ ፡ ይላል ። ከመካከልህ ፡ ቀንበርን ፡ ብታርቅ ፥ ጣትህንም ፡ ፲ መጥቀስ ፡ ብትተው ፥ ብታንጐራጕርም ፥ ነፍስህንም ፡ ለተራበ ፡ ብታፈስስ ፥ የተጨነቀውንም ፡ ነፍስ ፡ ብታጠግብ ፥ ብርሃንህ ፡ በጨለማ ፡ ይወጣል ፡ ጨለማህም ፡ እንደ ፡ ቀትር ፡ ፲፩ ይሆናል ። እግዚአብሔርም ፡ ሁልጊዜ ፡ ይመራሃል ፤ ነፍስህንም ፡ በመልካም ፡ ነገር ፡ ያጠግባል ፡ አጥንትህንም ፡ ያጠናል ፤ አንተም ፡ እንደሚጠጣ ፡ ገነት ፥ ውኃውም ፡ እንደማያቋርጥ ፡ ፲፪ ምንጭ ፡ ትሆናለህ ። ከዱሮ ፡ ዘመን ፡ የፈረሱት ፡ ስፍራዎች ፡ ይሠራሉ ፥ የብዙ ፡ ትውልድም ፡ መሠረት ፡ ይታነጻል ፤ አንተም ፦ ሰበራውን ፡ ጠጋኝ ፥ የመኖሪያ ፡ መንገድን ፡ አዳሽ ፡ ትባላለህ ።

፲፫ ፈቃድህን ፡ በተቀደሰው ፡ ቀኔ ፡ ከማድረግ ፡ እግርህን ፡ ከሰንበት ፡ ብትመልስ ፥ ሰንበትንም ፡ ደስታ ፥ እግዚአብሔርም ፡ የቀደሰውን ፡ ክቡር ፡ ብትለው ፥ የገዛ ፡ መንገድህንም ፡ ከማድረግ ፡ ፈቃድህንም ፡ ከማግኘት ፡ ከንቱ ፡ ነገርንም ፡ ከመናገር ፡ ተከልክለህ ፡ ብታከብረው ፥ ፲፬ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይልሃል ፥ በምድርም ፡ ከፍታዎች ፡ ላይ ፡ አወጣሃለሁ ፥ የአባትህንም ፡ የያዕቆብን ፡ ርስት ፡ አበላሃለሁ ፤ የእግዚአብሔር ፡ አፍ ፡ ተናግሮአልና ።

## ምዕራፍ ፡ ፶፱ ።

፩ እነሆ ፥ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ከማዳን ፡ አላጠረችም ፥ ጆሮውም ፡ ከመስማት ፡ አልደነቈረችም ፤ ፪ ነገር ፡ ግን ፡ በደላችሁ ፡ በእናንተና ፡ በአምላካችሁ ፡ መካከል ፡ ለይታለች ፥ እንዳይሰማም ፡ ኃጢአታችሁ ፡ ፊቱን ፡ ከእናንተ ፡ ሰውሮታል ። ፫ እጃችሁ ፡ በደም ፡ ጣታችሁም ፡ በበደል ፡ ረክሳለች ፥ ከንፈራችሁም ፡ ሐሰትን ፡ ተናግሮአል ፥ ምላሳችሁም ፡ ኃጢአትን ፡ አሰምቶአል ። ፬ በጽድቅ ፡ የሚጠራ ፡ በእውነትም ፡ የሚፈርድ ፡ የለም ፤ በምናምንቴ ፡ ነገር ፡ ታምነዋል ፡ ሐሰትንም ፡ ተናግረዋል ፤ ጒዳትን ፡ ፀንሰዋል ፡ በደልንም ፡ ወልደዋል ። ፭ የእባብን ፡ እንቍላል ፡ ቀፈቀፉ ፥ የሸረሪትንም ፡ ድር ፡ አደሩ ፤ እንቍላላቸውንም ፡ የሚበላ ፡ ሰው ፡ ይሞታል ፥ እንቍላሉም ፡ ሲሰበር ፡ እፉኝት ፡ ይወጣል ። ፮ ድሮቻቸውም ፡ ልብስ ፡ አይሆኑላቸውም ፥ በሥራቸውም ፡ አይሸፈኑም ፤ ሥራቸውም ፡ የበደል ፡ ሥራ ፡ ነው ፥ የግፍም ፡ ሥራ ፡ በእጃቸው ፡ ነው ። ፯ እግሮቻቸው ፡ ወደ ፡ ክፋት ፡ ይሮጣሉ ፥ ንጹሑን ፡ ደም ፡ ለማፍሰስ ፡ ይፈጥናሉ ፤ አሳባቸው ፡ የኃጢአት ፡ አሳብ ፡ ነው ፥ ጕስቍልናና ፡ ቅጥቃጤ ፡ በመንገዳቸው ፡ አለ ። ፰ የሰላምን ፡ መንገድ ፡ አያውቁም ፥ በአካሄዳቸውም ፡ ፍርድ ፡ የለም ፤ መንገዳቸውን ፡ አጣምመዋል ፥ የሚሄድበትም ፡ ሁሉ ፡ ሰላምን ፡ አያውቅም ።

፱ ስለዚህ ፡ ፍርድ ፡ ከእኛ ፡ ዘንድ ፡ ርቆአል ፥ ጽድቅም ፡ አላገኘንም ፤ ብርሃንን ፡ በተስፋ ፡ እንጠባበቅ ፡ ነበር ፥ እነሆም ፥ ጨለማ ፡ ሆነ ፤ ጸዳልን ፡ በተስፋ ፡ እንጠባበቅ ፡ ነበር ፥ ነገር ፡ ግን ፡ በጨለማ ፡ ሄድን ። ፲ እንደ ፡ ዕውሮች ፡ ወደ ፡ ቅጥሩ ፡ ተርመሰመስን ፥ ዓይን ፡ እንደሌላቸው ፡ ተርመሰመስን ፤ በቀትር ፡ ጊዜ ፡ በድግዝግዝታ ፡ እንዳለ ፡ ሰው ፡ ተሰናከልን ፥ እንደ ፡ ሙታን ፡ በጨለማ ፡ ስፍራ ፡ ነን ። ፲፩ ሁላችን ፡ እንደ ፡ ድቦች ፡ እንጮኻለን ፥ እንደ ፡ ርግብ ፡ እንልቃቀሳለን ፤ ፍርድን ፡ በተስፋ ፡ እንጠባበቅ ፡ ነበር ፡ እርሱም ፡ የለም ፤ መዳንም ፡ ከእኛ ፡ ዘንድ ፡ ርቆአል ። ፲፪ ዓመፃችን ፡ በአንተ ፡ ፊት ፡ በዝቶአልና ፥ ኃጢአታችን ፡ መስክሮብናልና ፥ ዓመፃችን ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ነውና ፥ በደላችንን ፡ እናውቃለንና ። ፲፫ ዐምፀናል ፥ ሐሰትን ፡ ተናግረ

ናል ፥ አምላካችንንም ፡ ከመከተል ፡ ተመልሰናል ፤ ግፍንና ፡ ዓመፅንም ፡ ተናግረናል ፥ የኃጢአት ፡ ቃልንም ፡ ፀንሰን ፡ ከልብ ፡ አውጥተናል ። ፲፬ ፍርድም ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ተመልሶአል ፥ ጽድቅም ፡ በሩቅ ፡ ቆሞአል ፤ እውነትም ፡ በአደባባይ ፡ ላይ ፡ ወድቆአልና ፥ ቅንነትም ፡ ሊገባ ፡ አልቻለምና ። ፲፭ እውነትም ፡ ታጥቶአል ፥ ከክፋትም ፡ የራቀ ፡ ሰው ፡ ለብዝበዛ ፡ ሆኖአል ።

እግዚአብሔርም ፡ አየ ፥ ፍርድም ፡ ስለሌለ ፡ ተከፋ ። ፲፮ ሰውም ፡ እንደሌለ ፡ አየ ፥ ወደ ፡ እርሱ ፡ የሚማልድ ፡ እንደሌለ ፡ ተረዳ ፡ ተደነቀም ፤ ስለዚህ ፡ የገዛ ፡ ክንዱ ፡ መድኀኒት ፡ አመጣለት ፥ ጽድቁም ፡ አገዘው ። ፲፯ ጽድቅንም ፡ እንደ ፡ ጥሩር ፡ ለበሰ ፥ በራሱም ፡ ላይ ፡ የማዳንን ፡ ራስ ፡ ቍር ፡ አደረገ ፤ የበቀልንም ፡ ልብስ ፡ ለበሰ ፥ በቅንዓትም ፡ መጐናጸፊያ ፡ ተጐናጸፈ ። ፲፰ እንደ ፡ ሥራቸው ፡ መጠን ፡ እንዲሁ ፡ ቍጣን ፡ ለባላጋራዎቹ ፥ ፍዳንም ፡ ለጠላቶቹ ፡ ይከፍላል ፤ ለደሴቶችም ፡ ፍዳቸውን ፡ ይከፍላል ። ፲፱ እርሱ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነፋስ ፡ እንደሚነዳው ፡ እንደ ፡ ጐርፍ ፡ ፈሳሽ ፡ ይመጣልና ፡ በምዕራብ ፡ ያሉት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፥ በፀሐይ ፡ መውጫም ፡ ያሉት ፡ ክብሩን ፡ ይፈራሉ ።

፳ ለጽዮን ፡ ታዳጊ ፡ ይመጣል ፥ በያዕቆብም ፡ ዘንድ ፡ ከኃጢአት ፡ ለሚርቁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፳፩ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ ቃል ፡ ኪዳኔ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ በአንተ ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ መንፈሴ ፡ በአፍህም ፡ ውስጥ ፡ ያደረግሁት ፡ ቃሌ ፡ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ ከአፍህ ፡ ከዘርህም ፡ አፍ ፡ ከዘር ፡ ዘርህም ፡ አፍ ፡ አያልፍም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፷ ።

፩ ብርሃንሽ ፡ መጥቶአልና ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ፪ ክብር ፡ ወጥቶልሻልና ፡ ተነሺ ፥ አብሪ ። እነሆ ፥ ጨለማ ፡ ምድርን ፡ ድቅድቅ ፡ ጨለማም ፡ አሕዛብን ፡ ይሸፍናል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በአንቺ ፡ ላይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይወጣል ፡ ክብሩም ፡ በአንቺ ፡ ፫ ላይ ፡ ይታያል ፤ አሕዛብም ፡ ወደ ፡ ብርሃንሽ ፡ ነገሥታትም ፡ ወደ ፡ መውጫሽ ፡ ጸዳል ፡ ይመጣሉ ።

፬ ዓይኖችሽን ፡ አንሥተሽ ፡ በዙሪያሽ ፡ ተመልከቺ ፤ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ተሰብስበው ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡ ይመጣሉ ፤ ወንዶች ፡ ልጆችሽ ፡ ከሩቅ ፡ ይመጣሉ ፥ ሴቶች ፡ ልጆችሽንም ፡ በጫንቃ ፡ ላይ ፡ ፭ ይሸከሙአቸዋል ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የባሕሩ ፡ በረከት ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡ ስለሚመለስ ፥ የአሕዛብም ፡ ብልጥግና ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡ ስለሚመጣ ፥ አይተሽ ፡ ደስ ፡ ይልሻል ፥ ልብሽም ፡ ይደነቃል ፡ ፮ ይሰፋማል ። የግመሎች ፡ ብዛት ፥ የምድያምና ፡ የጌፌር ፡ ግመሎች ፥ ይሸፍኑሻል ፤ ሁሉ ፡ ከሳባ ፡ ይመጣሉ ፥ ወርቅንና ፡ ዕጣንን ፡ ያመጣሉ ፡ የእ ፯ ግዚአብሔርንም ፡ ምስጋና ፡ ያወራሉ ። የቄዳር ፡ መንጎች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡ ይሰበሰባሉ ፡ የነበዮትም ፡ አውራ ፡ በጎች ፡ ያገለግሉሻል ፤ እኔን ፡ ደስ ፡ ሊያሰኙ ፡ በመሠዊያዬ ፡ ላይ ፡ ይወጣሉ ፥ የክብሬንም ፡ ቤት ፡ አከብራለሁ ።

፰ ርግቦች ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ እንደሚበርሩ ፥ እነዚህ ፡ እንደ ፡ ደመና ፡ የሚበርሩ ፡ እነማን ፡ ናቸው ? ፱ እርሱ ፡ አክብሮሻልና ፡ ለአምላክሽ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስምና ፡ ለእስራኤል ፡ ቅዱስ ፡ ልጆችሽን ፡ ከሩቅ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋርም ፡ ብራቸውንና ፡ ወርቃቸውን ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡ ደሴቶች ፡ የተርሴስ ፡ መርከቦችም ፡ አስቀድመው ፡ ይጠባበቁኛል ።

፲ በቍጣዬ ፡ ቀሥፌ ፡ በፍቅሬ ፡ ምሬሻለሁና ፡ መጻተኞች ፡ ቅጥርሽን ፡ ይሠራሉ ፥ ነገሥታቶቻቸውም ፡ ያገለግሉሻል ። ፲፩ በሮችሽም ፡ ሁል ጊዜ ፡ ይከፈታሉ ፤ ሰዎች ፡ የአሕዛብን ፡ ብልጥግና ፡ የተማረኩትንም ፡ ነገሥታቶቻቸውን ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡ ሌሊትና ፡ ቀን ፡ አይዘጉም ። ፲፪ ለአንቺም ፡ የማይገዛ ፡ ሕዝብና ፡ መንግሥት ፡ ይጠፋል ፥ እነዚያ ፡ አሕዛብም ፡ ፈጽመው ፡ ይጠፋሉ ። ፲፫ የመቅደሴንም ፡ ስፍራ ፡ ያስጌጡ ፡ ዘንድ ፡ የሊባኖስ ፡ ክብር ፥ ጥዱና ፡ አስታው ፡ በርሰነቱም ፥ ወደ ፡ አንቺ ፡ ይመጣሉ ፥ የእግሬንም ፡ ስፍራ ፡ አከብራለሁ ። ፲፬ የአስጨናቂዎችሽም ፡ ልጆች ፡ አንገታቸውን ፡ ደፍተው ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡ ይመጣሉ ፥ የናቁሽም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እግርሽ ፡ ጫማ ፡ ይሰግዳሉ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ከተማ ፥ የእስራኤል ፡ ቅዱስ ፡ የሆንሽ ፡ ጽዮን ፡ ይሉሻል ።

፲፭ ከሰውም ፡ ማንም ፡ እስከማያልፍብሽ ፡ ድረስ ፡ የተተውሽና ፡ የተጠላሽ ፡ ነበርሽ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የዘላለም ፡ ትምክሕትና ፡ የልጅ ፡ ልጅ ፡ ደስታ ፡ አደርግሻለሁ ። ፲፮ የአሕዛብንም ፡ ወተት ፡ ትጠጪያለሽ ፡ የነገሥታትንም ፡ ጡት ፡ ትጠቢያለሽ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ የያዕቆብ ፡ ኃያል ፥ መድኃኒትሽና ፡ ታዳጊሽ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቂያለሽ ። ፲፯ በናስ ፡ ፋንታ ፡ ወርቅን ፥ በብረትም ፡ ፋንታ ፡ ብርን ፥ በእንጨትም ፡ ፋንታ ፡ ናስን ፥ በድንጋይም ፡ ፋንታ ፡ ብረትን ፡ አመጣለሁ ። አለቆችሽንም ፡ ሰላም ፥ የበላይ ፡ ገዢዎችሽንም ፡ ጽድቅ ፡ አደርጋለሁ ፤ ፲፰ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ በምድርሽ ፡ ውስጥ ፡ ግፍ ፥ በዳርቻሽም ፡ ውስጥ ፡ ጕስቍልናና ፡ ቅጥቃጤ ፡ አይሰማም ፤ ቅጥርሽን ፡ መዳን ፡ በሮችሽንም ፡ ምስጋና ፡ ብለሽ ፡ ትጠሪያለሽ ። ፲፱ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ የዘላለም ፡ ብርሃንሽ ፥ አምላክሽም ፡ ክብርሽ ፡ ይሆናልና ፡ ፀሐይ ፡ በቀን ፡ ብርሃን ፡ አይሆንልሽም ፥ የጨረቃም ፡ ብርሃን ፡ በሌሊት ፡ አያበራልሽም ። ፳ እግዚአብሔር ፡ የዘላለም ፡ ብርሃንሽ ፡ ይሆናልና ፥ የልቅሶሽም ፡ ወራት ፡ ታልቃለችና ፡ ፀሐይሽ ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ አትጠልቅም ፡ ጨረቃሽም ፡ አይቋረጥም ። ፳፩ ሕዝብሽም ፡ ሁሉ ፡ ጻድቃን ፡ ይሆናሉ ፤ እኔም ፡ እከብር ፡ ዘንድ ፡ የአታክልቴን ፡ ቡቃያ ፥ የእጄ ፡ ሥራ ፡ የምትሆን ፡ ምድ

፳፪፤ ሬቱንም ፡ ለዘላለም ፡ ይወርሳሉ ። ታናሹ ፡ ለሺህ ፡
የሁሉም ፡ ታናሹ ፡ ለብርቱ ፡ ሕዝብ ፡ ይሆናል ፤
እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዘመኑ ፡ ይህን ፡ አፋጥነ
ዋለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፷፩ ።

፩፤ የጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ በእኔ ፡
ላይ ፡ ነው ፥ ለድሆች ፡ የምሥራችን ፡ እሰብክ ፡
ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቀብቶኛልና ፤ ልባቸው ፡
የተሰበረውን ፡ እጠግን ፡ ዘንድ ፥ ለተማረኩትም ፡
ነጻነትን ፡ ለታሰሩትም ፡ መፈታትን ፡ እናገር ፡
፪፤ ዘንድ ፡ ልኮኛል ። የተወደደችውን ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ዓመት ፡ አምላካችንም ፡ የሚበቀልበ
ትን ፡ ቀን ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፥ የሚያለቅሱትንም ፡
፫፤ ሁሉ ፡ አጽናና ፡ ዘንድ ፤ እግዚአብሔር ፡ ለክ
ብሩ ፡ የተከላቸው ፡ የጽድቅ ፡ ዛፎች ፡ እንዲ
ባሉ ፡ ለጽዮን ፡ አልቃሾች ፡ አደርግላቸው ፡
ዘንድ ፥ በአመድ ፡ ፋንታ ፡ አክሊልን ፥ በልቅ
ሶም ፡ ፋንታ ፡ የደስታን ፡ ዘይት ፥ በኀዘንም ፡
መንፈስ ፡ ፋንታ ፡ የምስጋናን ፡ መጐናጸፊያ ፡
እሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ልኮኛል ።
፬፤ ከጥንትም ፡ ጀምሮ ፡ ባድማ ፡ የነበሩትን ፡ ይሠ
ራሉ ፡ ከቀድሞ ፡ የፈረሱትንም ፡ ያቆማሉ ፤
ባድማ ፡ የነበሩትንና ፡ ከብዙ ፡ ትውልድ ፡ በፊት ፡
የፈረሱትን ፡ ከተሞች ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ይሠራሉ ።
፭፤ መጻተኞችም ፡ ቆመው ፡ በጎቻችሁን ፡ ያሰማ
ራሉ ፥ ሌሎች ፡ ወገኖችም ፡ አራሾችና ፡ ወይን ፡
፮፤ ጠባቂዎች ፡ ይሆኑላችኋል ። እናንተ ፡ ግን ፡ የእ
ግዚአብሔር ፡ ካህናት ፡ ትባላላችሁ ፥ ሰዎቹም ፡
የአምላካችን ፡ አገልጋዮች ፡ ብለው ፡ ይጠሩአ
ችኋል ፤ የአሕዛብን ፡ ሀብት ፡ ትበላላችሁ ፥ በክ
፯፤ ብራቸውም ፡ ትመካላችሁ ። በእፍረታችሁ ፡
ፋንታ ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ ይሆንላችኋል ፥ በውር
ደታችሁም ፡ ፋንታ ፡ ዕድል ፡ ፈንታችሁ ፡ ደስ ፡
ይላቸዋል ፤ ስለዚህ ፡ በምድራቸው ፡ ሁለት ፡
እጥፍ ፡ ይገዛሉ ፥ የዘላለምም ፡ ደስታ ፡ ይሆንላ
፰፤ ቸዋል ። እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፍርድን ፡ የም
ወድድ ፡ ስርቆትንና ፡ በደልን ፡ የምጠላ ፡ ነኝ ፤
ፍዳቸውንም ፡ በእውነት ፡ እሰጣቸዋለሁ ፥ ከእ
ነርሱም ፡ ጋር ፡ የዘላለምን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደ
፱፤ ርጋለሁ ። ዘራቸውም ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፥
ልጆቻቸውም ፡ በወገኖች ፡ መካከል ፡ የታወቁ ፡
ይሆናሉ ፤ ያያቸው ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ የባ
ረካቸው ፡ ዘር ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ይገነዘባል ።
፲፤ አክሊልን ፡ እንደ ፡ ለበሰ ፡ ሙሽራ ፥ በጌጥ ፡
ሽልማትዋም ፡ እንዳጌጠች ፡ ሙሽራ ፥ የማዳ
ንን ፡ ልብስ ፡ አልብሶኛልና ፥ የጽድቅንም ፡ መጐ
ናጸፊያ ፡ ደርቦልኛልና ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅግ ፡
ደስ ፡ ይለኛል ፥ ነፍሴም ፡ በአምላኬ ፡ ሐሤት ፡
፲፩፤ ታደርጋለች ። ምድርም ፡ ቡቃያዋን ፡ እንደም
ታወጣ ፥ ገነትም ፡ ዘሩን ፡ እንደሚያበቅል ፥
እንዲሁ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጽድቅንና ፡ ምስ
ጋናን ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ያበቅላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፷፪ ።

፩፤ ስለ ፡ ጽዮን ፡ ዝም ፡ አልልም ፥ ስለ ፡ ኢየሩ
ሳሌምም ፡ ጸጥ ፡ አልልም ፥ ጽድቅዋ ፡ እንደ ፡
ጸዳል ፡ መዳንዋም ፡ እንደሚበራ ፡ ፋና ፡ እስኪ
፪፤ ወጣ ፡ ድረስ ። አሕዛብም ፡ ጽድቅሽን ፡ ነገሥ
ታትም ፡ ሁሉ ፡ ክብርሽን ፡ ያያሉ ፤ የእግዚአብ
ሔርም ፡ አፍ ፡ በሚጠራበት ፡ በአዲሱ ፡ ስም ፡
፫፤ ትጠሪያለሽ ። በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ የክብር ፡
አክሊል ፥ በአምላክሽም ፡ እጅ ፡ የመንግሥት ፡
፬፤ ዘውድ ፡ ትሆኛለሽ ። ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡—
የተተወች ፡ አትባዪም ፤ ምድርሽም ፡ ከእንግ
ዲህ ፡ ወዲህ ፡— ውድማ ፡ አትባልም ፤ ነገር ፡
ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ በአንቺ ፡ ደስ ፡ ብሎታ
ልና ፥ ምድርሽም ፡ ባል ፡ ታገባለችና ፡ አንቺ ፡—
ደስታዬ ፡ የሚኖርባት ፡ ትባያለሽ ፡ ምድርሽም ፡—
፭፤ ባል ፡ ያገባች ፡ ትባላለች ። ጕልማሳም ፡ ድንግ
ሊቱን ፡ እንደሚያገባ ፥ እንዲሁ ፡ ልጆችሽ ፡ ያገ
ቡሻል ፤ ሙሽራም ፡ በሙሽራይቱ ፡ ደስ ፡ እንደ
ሚለው ፥ እንዲሁ ፡ አምላክሽ ፡ በአንቺ ፡ ደስ ፡
ይለዋል ።
፮፤፯፤ ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ፥ ጕበኞችን ፡ በቅጥርሽ ፡
ላይ ፡ አቁሜአለሁ ፤ ቀንና ፡ ሌሊት ፡ ከቶ ፡ ዝም ፡
አይሉም ፤ እናንተ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምታ
ሳስቡ ፥ ኢየሩሳሌምን ፡ እስኪያጸና ፡ በምድ
ርም ፡ ላይ ፡ ምስጋና ፡ እስኪያደርጋት ፡ ድረስ ፡
፰፤ አትረፉ ፡ ለእርሱም ፡ ዕረፍት ፡ አትስጡ ። እግ
ዚአብሔር ፡— ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ በእርግጥ ፡
ለጠላቶችሽ ፡ መብል ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ እህልሽን ፡
አልሰጥም ፥ መጻተኞችም ፡ የደከምሽበትን ፡
፱፤ ወይንሽን ፡ አይጠጡም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የሰበሰ
ቡት ፡ ይበሉታል ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ያመሰ
ግናሉ ፥ ያከማቹትም ፡ በመቅደሴ ፡ አደባባይ ፡
ላይ ፡ ይጠጡታል ፡ ብሎ ፡ በቀኙና ፡ በኃይሉ ፡
ክንድ ፡ ምሎአል ።
፲፤ እለፉ ፥ በበሮች ፡ በኩል ፡ እለፉ ፤ የሕዝቡ
ንም ፡ መንገድ ፡ ጥረጉ ፤ አዘጋጁ ፥ ጐዳናውን ፡
አዘጋጁ ፥ ድንጋዮቹንም ፡ አስወግዱ ፤ ለአሕዛ
፲፩፤ ብም ፡ ዓላማ ፡ አንሡ ። እነሆ ፥ እግዚአብሔር ፡
ለምድር ፡ ዳርቻ ፡ አዋጅ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ነግ
ሮአል ፡— ለጽዮን ፡ ልጅ ፡— እነሆ ፥ መድኃኒ
ትሽ ፡ ይመጣል ፤ እነሆ ፥ ዋጋው ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
፲፪፤ ሥራውም ፡ በፊቱ ፡ አለ ፡ በሉአት ። እግዚአ
ብሔር ፡— የተቤዣቸው ፥ የተቀደሰ ፡ ሕዝብ ፡
ብለው ፡ ይጠሩአቸዋል ፤ አንቺም ፡— የተፈለ
ገች ፡ ያልተተወችም ፡ ከተማ ፡ ትባያለሽ ።

## ምዕራፍ ፡ ፷፫ ።

፩፤ ይህ ፡ ከኤዶምያስ ፥ ልብሱም ፡ የቀላ ፡ ከባ
ሶራ ፡ የሚመጣ ፥ አለባበሱ ፡ ያማረ ፥ በጕልበቱ ፡
ጽናት ፡ የሚራመድ ፡ ማን ፡ ነው ? በጽድቅ ፡
የምናገር ፡ ለማዳንም ፡ የምበረታ ፡ እኔ ፡ ነኝ ።
፪፤ ቀሚስህ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ቀላ ? ልብስህስ ፡ በወይን ፡
መጥመቂያ ፡ እንደሚረግጥ ፡ ሰው ፡ ልብስ ፡ ስለ ፡

፫ ምን ፡ መሰለ ? መጥመቂያውን ፡ ብቻዬን ፡ ረግ
ጫለሁ ፥ ከአሕዛብም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ከእኔ ፡
ጋር ፡ አልነበረም ፤ በቍጣዬ ፡ ረገጥኋቸው ፡
በመዓቴም ፡ ቀጠቀጥኋቸው ፤ ደማቸውም ፡ በል
ብሴ ፡ ላይ ፡ ተረጭቶአል ፥ ልብሴንም ፡ ሁሉ ፡
፬ አሳድፌአለሁ ። የምበቀልበት ፡ ቀን ፡ በልቤ ፡
ነውና ፥ የምቤዥበትም ፡ ዓመት ፡ ደርሶአልና ።
፭ ተመለከትሁ ፥ የሚረዳም ፡ አልተገኘም ፤ የሚ
ያግዝም ፡ አልነበረምና ፡ ተደነቅሁ ፤ ስለዚህ ፡
የገዛ ፡ ክንዴ ፡ መድኃኒት ፡ አመጣልኝ ፥ ቍጣ
፮ ዬም ፡ እርሱ ፡ አገዘኝ ። በቍጣዬም ፡ አሕዛብን ፡
ረገጥሁ ፡ በመዓቴም ፡ ቀጠቀጥኋቸው ፥ ደማቸ
ውንም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ አፈሰስሁት ።
፯ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሰጠን ፡ ሁሉ ፥ የእግ
ዚአብሔርን ፡ ቸርነትና ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ምስጋና ፥ እንደ ፡ ምሕረቱና ፡ እንደ ፡ ቸርነ
ቱም ፡ ብዛት ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ የሰጠውን ፡
፰ ትልቅ ፡ በጎነት ፡ አሳስባለሁ ። እርሱም ፡— በእ
ውነት ፡ ሕዝቤ ፥ ሐሰትን ፡ የማያደርጉ ፡ ልጆች ፥
፱ ናቸው ፡ አለ ፤ መድኃኒትም ፡ ሆነላቸው ። በጭ
ንቃቸው ፡ ሁሉ ፡ እርሱ ፡ ተጨነቀ ፥ የፊቱም ፡
መልአክ ፡ አዳናቸው ፤ በፍቅሩና ፡ በርኅራኄ
ውም ፡ ተቤዣቸው ፥ በቀደመውም ፡ ዘመን ፡
ሁሉ ፡ አንሥቶ ፡ ተሸከማቸው ።
፲ እነርሱ ፡ ግን ፡ ዐመፁ ፡ ቅዱስ ፡ መንፈሱንም ፡
አስመረሩ ፤ ስለዚህ ፡ ተመልሶ ፡ ጠላት ፡ ሆና
፲፩ ቸው ፥ እርሱም ፡ ተዋጋቸው ። እርሱም ፡ እን
ዲህ ፡ ብሎ ፡ የቀደመውን ፡ ዘመን ፡ አሰበ ፡— የበጎ
ቹን ፡ እረኛ ፡ ከባሕሩ ፡ ያወጣው ፡ ወዴት ፡ ነው ፡
ያለ ? ቅዱስ ፡ መንፈሱንም ፡ በመካከላቸው ፡
፲፪ ያኖረ ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ ያለ ? የከበረውንም ፡
ክንድ ፡ በሙሴ ፡ ቀኝ ፡ ያስሄደ ፥ ለራሱም ፡ የዘላ
ለምን ፡ ስም ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ውኃውን ፡ በፊ
፲፫ ታቸው ፡ የከፈለ ፥ በምድረ ፡ በዳም ፡ እንደሚ
ያልፍ ፡ ፈረስ ፥ በቀላይ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ ዕንቅ
፲፬ ፋት ፡ ያሳለፋቸው ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ ያለ ? ወደ ፡
ሸለቆ ፡ እንደሚወርዱ ፡ ከብቶች ፥ እንዲሁ ፡
የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ወደ ፡ ዕረፍት ፡ አመ
ጣቸው ፤ እንዲሁም ፡ ለራስህ ፡ የከበረ ፡ ስም ፡
ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝብን ፡ መራህ ።
፲፭ ከሰማይ ፡ ተመልከት ፥ ከቅዱስነትህና ፡ ከክብ
ርህም ፡ ማደሪያ ፡ ጐብኝ ፤ ቅንዓትህና ፡ ኃይል
ህስ ፡ ወዴት ፡ ነው ? ለእኔም ፡ የሆነው ፡ የልብህ ፡
፲፮ ናፍቆትና ፡ ርኅራኄህ ፡ ተከለከለ ። አብርሃም ፡
ባያውቀን ፡ እስራኤልም ፡ ባይገነዘበን ፡ አንተ ፡
አባታችን ፡ ነህ ፤ አቤቱ ፥ አንተ ፡ አባታችን ፡
ነህ ፥ ስምህም ፡ ከዘላለም ፡ ታዳጊያችን ፡ ነው ።
፲፯ አቤቱ ፥ ከመንገድህ ፡ ለምን ፡ አሳትኸን ? እንዳ
ንፈራህም ፡ ልባችንን ፡ ለምን ፡ አጸናህብን ? ስለ ፡
ባሪያዎችህ ፡ ስለ ፡ ርስትህ ፡ ነገዶች ፡ ተመለስ ።
፲፰ የተቀደሰው ፡ ሕዝብህ ፡ መቅደስህን ፡ ጥቂት ፡
ጊዜ ፡ ወረሱት ፤ ጠላቶቻችንም ፡ ረግጠውታል ።
፲፱ ከዘላለም ፡ እንዳልገዛኸን ፡ በስምህም ፡ እንዳል
ተጠራን ፡ ሆነናል ።

ምዕራፍ ፡ ፷፬ ።

፩ ሰማዮችን ፡ ቀድደህ ፡ ምነው ፡ ብትወርድ !
፪ ተራሮችም ፡ ምነው ፡ ቢናወጡ ! እሳት ፡ ጭራ
ሮውን ፡ እንደሚያቃጥል ፥ እሳትም ፡ ውኃውን ፡
እንደሚያፈላ ፥ ስምህ ፡ ለጠላቶችህ ፡ ይገለጥ ፡
ዘንድ ፥ አሕዛብም ፡ በፊትህ ፡ ይንቀጠቀጡ ፡
፫ ዘንድ ። ያልተጠባበቅነውን ፡ የክብርህን ፡ ሥራ ፡
በደረግህ ፡ ጊዜ ፥ ወረድህ ፡ ተራሮችም ፡ በፊ
፬ ትህ ፡ ተንቀጠቀጡ ። ሰዎች ፡ ከጥንት ፡ጀምሮ ፡
ለሚጠብቁህ ፡ ከምትሠራላቸው ፡ ከአንተ ፡
በቀር ፡ ሌላ ፡ አምላክን ፡ አልሰሙም ፡ በጆሮአ
ቸውም ፡ አልተቀበሉም ፡ ዓይንም ፡ አላየችም ።
፭ ጽድቅን ፡ የሚያደርገውን ፡ በመንገዶችህም ፡
የሚያስቡህን ፡ ትገናኛቸዋለህ ። እነሆ ፥ አንተ ፡
ተቈጣህ ፡ እኛም ፡ ኃጢአት ፡ ሠራን ፤ ስለዚ
፮ ህም ፡ ተሳሳትን ። ሁላችን ፡ እንደ ፡ ርኩስ ፡
ሰው ፡ ሆነናል ፥ ጽድቃችንም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡
መርገም ፡ ጨርቅ ፡ ነው ፤ ሁላችንም ፡ እንደ ፡
ቅጠል ፡ ረግፈናል ፥ በደላችንም ፡ እንደ ፡ ነፋስ ፡
፯ ወስዶናል ። ስምህንም ፡ የሚጠራ ፥ አንተንም ፡
ሊይዝ ፡ የሚያስብ ፡ የለም ፤ ፊትህንም ፡ ከእኛ ፡
ሰውረሃል ፥ በኃጢአታችንም ፡ አጥፍተኸናል ።
፰ አሁን ፡ ግን ፥ አቤቱ ፥ አንተ ፡ አባታችን ፡
ነህ ፤ እኛ ፡ ጭቃ ፡ ነን ፡ አንተም ፡ ሠሪያችን ፡
ነህ ፥ እኛም ፡ ሁላችን ፡ የእጅህ ፡ ሥራ ፡ ነን ።
፱ አቤቱ ፥ እጅግ ፡ አትቈጣ ፥ ለዘላለምም ፡ ኃጢ
አትን ፡ አታስብ ፤ እነሆ ፥ እባክህ ፥ ተመልከት ፥
፲ እኛ ፡ ሁላችን ፡ ሕዝብህ ፡ ነን ። የተቀደሱ ፡ ከተ
ሞችህ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሆነዋል ፤ ጽዮን ፡ ምድረ ፡
በዳ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ውድማ ፡ ሆናለች ።
፲፩ አባቶቻችን ፡ አንተን ፡ ያመሰገኑበት ፡ የተቀደ
ሰና ፡ የተዋበ ፡ ቤታችን ፡ በእሳት ፡ ተቃጥሎ
አል ፥ ያማረውም ፡ ስፍራችን ፡ ሁሉ ፡ ፈርሶአል ።
፲፪ አቤቱ ፥ በውኑ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ትታገሣለህን ?
ዝምስ ፡ ትላለህን ? አጥብቀህስ ፡ ታስጨንቀና
ለህን ?

ምዕራፍ ፡ ፷፭ ።

፩ ላልጠየቁኝ ፡ ተገለጥሁ ፥ ላልፈለጉኝም ፡
ተገኘሁ ፤ በስሜም ፡ ያልተጠራውን ፡ ሕዝብ ፡—
፪ እነሆኝ ፥ እነሆኝ ፡ አልሁት ። መልካም ፡ ባል
ሆነው ፡ መንገድ ፥ አሳባቸውን ፡ እየተከተሉ ፥
ወደሚሄዱ ፡ ወደ ፡ ዓመፀኛ ፡ ሕዝብ ፡ ቀኑን ፡
፫ ሁሉ ፡ እጆቼን ፡ ዘረጋሁ ። ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ዘወ
ትር ፡ የሚያስቈጡኝ ፡ ናቸው ፤ እነርሱ ፡ በአት
ክልት ፡ ውስጥ ፡ የሚሠዉ ፡ በጡብም ፡ ላይ ፡
፬ የሚያጥኑ ፥ በመቃብርም ፡ መካከል ፡ የሚቀ
መጡ ፥ በስውርም ፡ ስፍራ ፡ የሚያድሩ ፥ የእ
ሪያ ፡ ሥጋም ፡ የሚበሉ ፡ ናቸው ። የረከሰው ፡
፭ መረቅ ፡ በዕቃቸው ፡ ውስጥ ፡ አለ ። እነርሱም ፡—
ለራስህ ፡ ቁም ፥ እኔ ፡ ከአንተ ፡ ይልቅ ፡ ቅዱስ ፡
ነኝና ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አትቅረብ ፡ ይላሉ ፤ እነዚህ ፡
በአፍንጫዬ ፡ ዘንድ ፡ ጢስ ፡ ቀኑንም ፡ ሁሉ ፡

፮ የምትነድድ ፡ እሳት ፡ ናቸው ። እነሆ ፥ በፊቴ ፡ ተጽፎአል ፤— ኃጢአታችሁንና ፡ የአባቶቻችሁን ፡ ኃጢአት ፡ በአንድ ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ብብታቸው ፡ ፍዳ ፡ አደርጌ ፡ እመልሳለሁ ፡ እንጂ ፡ ዝም ፡ አልልም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤

፯ በተራሮችም ፡ ላይ ፡ ስላጠኑ ፥ በኮረብቶችም ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ሰደቡኝ ፥ ስለዚህ ፡ አስቀድመው ፡ የሠሩትን ፡ ሥራቸውን ፡ በብብታቸው ፡ እሰፍራለሁ ።

፰ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፤— ወይን ፡ በዘለላው ፡ በተገኘች ፡ ጊዜ ፤— በረከት ፡ በእርስዋ ፡ ላይ ፡ አለና ፡ አታጥፉት ፡ እንደሚባለው ፥ ሁሉን ፡ እንዳላጠፉ ፡ ስለ ፡ ባሪያዎቼ ፡ እንዲሁ ፡ አደርጋለሁ ። ፱ ከያዕቆብም ፡ ዘርን ፡ ከይሁዳም ፡ ተራሮቼን ፡ የሚወርሰውን ፡ አወጣለሁ ፤ እኔም ፡ የመረጥኋቸው ፡ ይወርሱአታል ፥ ባሪያዎቼም ፡ በዚያ ፡ ይኖራሉ ። ፲ ሳሮንም ፡ የበጎች ፡ ማሰማርያ ፥ የአኮርም ፡ ሸለቆ ፡ የላሞች ፡ መመሰግያ ፡ ለፈለጉኝ ፡ ሕዝቤ ፡ ይሆናል ። ፲፩ እናንተን ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ የተዋችሁትን ፥ ቅዱሱንም ፡ ተራራዬን ፡ የረሳችሁትን ፥ ጉድ ፡ ለተባለ ፡ ጣዖትም ፡ ማዕድ ፡ ያዘጋጃችሁትን ፥ እድል ፡ ለተባለ ፡ ጣዖትም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ለመጠጥ ፡ ቍርባን ፡ የቀዳችሁትን ፥ ፲፪ እድላችሁን ፡ ለሰይፍ ፡ አደርገዋለሁ ፥ ሁላችሁም ፡ ለመታረድ ፡ ትጐነበሳላችሁ ፤ በፊቴም ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ አደረጋችሁ ፥ ያልወደድሁትንም ፡ መረጣችሁ ፡ እንጂ ፡ በጠራሁ ፡ ጊዜ ፡ አልመለሳችሁልኝምና ፥ በተናገርሁም ፡ ጊዜ ፡ አልሰማችሁኝምና ።

፲፫ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፤— እነሆ ፥ ባሪያዎቼ ፡ ይበላሉ ፡ እናንተ ፡ ግን ፡ ትራባላችሁ ፤ እነሆ ፥ ባሪያዎቼ ፡ ይጠጣሉ ፡ እናንተ ፡ ግን ፡ ትጠማላችሁ ፤ እነሆ ፥ ባሪያዎቼ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡ እናንተ ፡ ግን ፡ ታፍራላችሁ ፤ ፲፬ እነሆ ፥ ባሪያዎቼ ፡ ከልባቸው ፡ ደስታ ፡ የተነሣ ፡ ይዘምራሉ ፥ እናንተ ፡ ግን ፡ ከልባችሁ ፡ ኀዘን ፡ የተነሣ ፡ ትጮኻላችሁ ፥ መንፈሳችሁም ፡ ስለ ፡ ተሰበረ ፡ ወዮ ፡ ትላላችሁ ። ፲፭ ስማችሁንም ፡ ለተመረጡት ፡ ሕዝቤ ፡ እርግማን ፡ አድርጋችሁ ፡ ትተዋላችሁ ፥ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ይገድላችኋል ፥ ባሪያዎቹንም ፡ በሌላ ፡ ስም ፡ ይጠራቸዋል ። ፲፮ እንዲሁም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የተባረከ ፡ በእውነት ፡ አምላክ ፡ ይባረካል ፥ በምድርም ፡ ላይ ፡ የማለ ፡ በእውነት ፡ አምላክ ፡ ይምላል ፤ የቀድሞው ፡ ጭንቀት ፡ ተረስቶአልና ፥ ከዓይኔም ፡ ተሰውሮአልና ።

፲፯ እነሆ ፥ አዲስ ፡ ሰማይና ፡ አዲስ ፡ ምድር ፡ እፈጥራለሁና ፤ የቀደሙትም ፡ አይታሰቡም ፥ ወደ ፡ ልብም ፡ አይገቡም ። ፲፰ ነገር ፡ ግን ፡ በፈጠርሁት ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ለዘላለምም ፡ ሐሤት ፡ አድርጉ ፤ እነሆ ፥ ኢየሩሳሌምን ፡ ለሐሤት ፥ ሕዝብዋንም ፡ ለደስታ ፡ እፈጥራለሁና ። ፲፱ እኔም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ሐሤት ፡ አደርጋለሁ ፡ በሕዝቤም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፤ ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ የልቅሶ ፡ ድምፅና ፡ የዋይታ ፡ ድምፅ ፡ አይሰማባትም ። ፳ ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ ጥቂት ፡ ዘመን ፡ ብቻ ፡ የሚኖር ፡ ሕፃን ፥ ወይም ፡ ዕድሜውን ፡ ያልፈጸመ ፡ ሽማግሌ ፡ አይገኝም ፤ ጕልማሰው ፡ የመቶ ፡ ዓመት ፡ ሆኖት ፡ ይሞታልና ፥ ኃጢአተኛውም ፡ የመቶ ፡ ዓመት ፡ ሆኖት ፡ የተረገመ ፡ ይሆናልና ። ፳፩ ቤቶችንም ፡ ይሠራሉ ፡ ይቀመጡባቸውማል ፤ ወይኑንም ፡ ይተክላሉ ፡ ፍሬውንም ፡ ይበላሉ ። ፳፪ ሌላ ፡ እንዲቀመጥበት ፡ አይሠሩም ፥ ሌላም ፡ እንዲበላው ፡ አይተክሉም ፤ የሕዝቤ ፡ ዕድሜ ፡ እንደ ፡ ዛፍ ፡ ዕድሜ ፡ ይሆናልና ፥ እኔም ፡ የመረጥኋቸው ፡ በእጃቸው ፡ ሥራ ፡ ረጅም ፡ ዘመን ፡ ደስ ፡ ይላቸዋልና ። ፳፫ እነርሱ ፡ ከነልጆቻቸው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቡሩካን ፡ ዘር ፡ ናቸውና ፡ በከንቱ ፡ አይደክሙም ፡ ለጥፋትም ፡ አይወልዱም ። ፳፬ እንዲህም ፡ ይሆናል ፤ ሳይጠሩ ፡ እመልስላቸዋለሁ ፥ ገናም ፡ ሲናገሩ ፡ እሰማለሁ ። ፳፭ ተኵላና ፡ ጠቦት ፡ በአንድነት ፡ ይሰማራሉ ፥ አንበሳም ፡ እንደ ፡ በሬ ፡ ገለባ ፡ ይበላል ፥ የእባብም ፡ መብል ፡ ትቢያ ፡ ይሆናል ። በተቀደሰው ፡ ተራራዬ ፡ ሁሉ ፡ አይጐዱም ፥ አያጠፉምም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፷፮ ።

፩ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፤— ሰማይ ፡ ዙፋኔ ፡ ነው ፥ ምድርም ፡ የእግሬ ፡ መረገጫ ፡ ናት ፤ የምትሠሩልኝ ፡ ቤት ፡ ምን ፡ ዓይነት ፡ ነው ? የማርፍበትስ ፡ ስፍራ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ፪ እነዚህን ፡ ሁሉ ፡ እጄ ፡ ሠርታለችና ፡ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የእኔ ፡ ናቸው ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ወደዚህ ፡ ወደ ፡ ትሑት ፥ መንፈሱም ፡ ወደ ፡ ተሰበረ ፥ በቃሌም ፡ ወደሚንቀጠቀጥ ፡ ሰው ፡ እመለከታለሁ ። ፫ በሬን ፡ የሚያርድልኝ ፡ ሰውን ፡ እንደሚገድል ፡ ነው ፤ ጠቦትንም ፡ የሚሠዋ ፡ የውሻውን ፡ አንገት ፡ እንደሚሰብር ፡ ነው ፤ የእህልን ፡ ቍርባን ፡ የሚያቀርብ ፡ የእርያን ፡ ደም ፡ እንደሚያቀርብ ፡ ነው ፤ ዕጣንን ፡ የሚያጥን ፡ ጣዖትን ፡ እንደሚባርክ ፡ ነው ። እነዚህ ፡ የገዛ ፡ መንገዳቸውን ፡ መረጡ ፤ ነፍሳቸውም ፡ በርኵሰታቸው ፡ ደስ ፡ ይላታል ፤ ፬ እኔ ፡ ደግሞ ፡ የተሳለቀብቸውን ፡ እመርጣለሁ ፥ የፈሩትንም ፡ ነገር ፡ አመጣባቸዋለሁ ፤ በፊቴ ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ አደረጉ ፥ ያልወደድሁትንም ፡ መረጡ ፡ እንጂ ፡ በጠራሁ ፡ ጊዜ ፡ አልመለሱልኝምና ፥ በተናገርሁም ፡ ጊዜ ፡ አልሰሙኝምና ።

፭ በቃሉ ፡ የምትንቀጠቀጡ ፡ ሆይ ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስሙ ፤— የጠሉአችሁ ፡ ስለ ፡ ስሜም ፡ ያባረሩአችሁ ፡ ወንድሞቻችሁ ፤— ደስታችሁን ፡ እናይ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይከበር ፡ ብለዋል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ያፍራሉ ። ፮ የጩኸት ፡ ድምፅ ፡ ከከተማ ፥ ድምፅም ፡ ከመቅደስ ፥ በጠላቶቹ ፡ ላይ ፡ ፍዳን ፡ የሚያመጣ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ ተሰምቶአል ።

፯ ሳታምጥ ፡ ወለደች ፤ ምጥም ፡ ሳያገኛት ፡
፰ ወንድ ፡ ልጅን ፡ ወለደች ። ከቶ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡
ነገር ፡ ማን ፡ ሰምቶአል ? እንዲህስ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡
ማን ፡ አይቶአል ? በውኑ ፡ አገር ፡ በአንድ ፡ ቀን ፡
ታምጣለችን ? ወይስ ፡ በአንድ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝብ ፡
ይወለዳልን ? ጽዮን ፡ እንዳማጠች ፡ ወዲያው ፡
፱ ልጆችዋን ፡ ወልዳለችና ። በውኑ ፡ ወደ ፡ መው
ለድ ፡ የማደርስ ፡ እኔ ፡ አላስወልድምን ? ይላል ፡
እግዚአብሔር ፤ የማስወልድስ ፡ ማኅፀንን ፡ እኔ ፡
እዘጋለሁን ? ይላል ፡ አምላክሽ ።
፲ እናንተ ፡ የምትወድዱአት ፡ ሁሉ ፥ ከኢየሩ
ሳሌም ፡ ጋር ፡ ሐሤትን ፡ አድርጉ ፥ ስለ ፡ እርስ
ዋም ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፤ እናንተም ፡ የምታለቅ
ሱላት ፡ ሁሉ ፥ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ በደስታ ፡ ሐሤ
፲፩ ትን ፡ አድርጉ ፥ ትጠቡ ፡ ዘንድ ፡ ከማጽናናት
ዋም ፡ ጡት ፡ ትጠግቡ ፡ ዘንድ ፤ እጅግ ፡ ጠጥታ
ችሁ ፡ በክብርዋ ፡ሙላት ፡ ደስ ፡ ይላችሁ ፡ ዘንድ ።
፲፪ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— እነሆ ፥
ሰላምን ፡ እንደ ፡ ወንዝ ፥ የአሕዛብንም ፡ ክብር ፡
እንደሚጐርፍ ፡ ፈሳሽ ፡ እመልስላታለሁ ፤ ከዚ
ያም ፡ ትጠባላችሁ ፥ በጫንቃ ፡ ላይ ፡ ይሸከሙ
አችኋል ፡ በጕልበትም ፡ ላይ ፡ እያስቀመጡ ፡
፲፫ ያቀማጥሉአችኋል ። እናት ፡ ልጅዋን ፡ እንደ
ምታጽናና ፡ እንዲሁ ፡ አጽናናችኋለሁ ፥ በኢየ
፲፬ ሩሳሌምም ፡ ውስጥ ፡ ትጽናናላችሁ ። ታያላ
ችሁ ፥ ልባችሁም ፡ ሐሤት ፡ ታደርጋለች ፥ አጥ
ንታችሁም ፡ እንደ ፡ ለምለም ፡ ሣር ፡ ትበቅላ
ለች ፤ የእግዚአብሔርም ፡ እጅ ፡ ለሚፈሩት ፡
ትታወቃለች ፥ በጠላቶቹም ፡ ላይ ፡ ይቈጣል ።
፲፭ እነሆ ፥ እግዚአብሔር ፡ መዓቱን ፡ በቍጣ ፥
ዘለፋውንም ፡ በእሳት ፡ ነበልባል ፡ ይመልስ ፡
ዘንድ ፡ ከእሳት ፡ ጋር ፡ ይመጣል ፥ ሰረገሎቹም ፡
፲፮ እንደ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ይሆናሉ ። እግዚአብ
ሔርም ፡ በሥጋ ፡ ለባሽ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በእሳትና ፡
በሰይፉ ፡ ይፈርዳል ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ተወ
፲፯ ግተው ፡ የሞቱት ፡ ይበዛሉ ። በመካከላቸው ፡
ያለውን ፡ አንዱን ፡ ተከትለው ፡ ወደ ፡ ገነቱ ፡
ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ ሰውነታቸውን ፡ የሚቀድሱና ፡
የሚያነጹ ፥ የእሪያንም ፡ ሥጋ ፡ አስጸያፊ ፡ ነገ
ርንም ፡ አይጥንም ፡ የሚበሉ ፡ በአንድነት ፡ ይጠ
ፋሉ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
፲፰ ሥራቸውንና ፡ አሳባቸውን ፡ አውቄአለሁና ፤
አሕዛብንና ፡ ልሳናትን ፡ ሁሉ ፡ የምሰበስብበት ፡
ጊዜ ፡ ይደርሳል ፥ እነርሱም ፡ ይመጣሉ ፡ ክብ
፲፱ ሬንም ፡ ያያሉ ። በመካከላቸውም ፡ ምልክት ፡
አደርጋለሁ ፥ ከእነርሱም ፡ የዳኑትን ፡ ዝናዬን ፡
ወዳልሰሙ ፥ ክብሬንም ፡ ወዳላዩ ፡ ወደ ፡ አሕዛብ ፡
ወደ ፡ ተርሴስ ፡ ወደ ፡ ፉጥ ፡ ወደ ፡ ሉድ ፡ ወደ ፡
ሞሳሕ ፡ ወደ ፡ ቶቤል ፡ ወደ ፡ ያዋን ፡ በሩቅ ፡
ወዳሉ ፡ ደሴቶች ፡ እልካቸዋለሁ ፥ በአሕዛብም ፡
፳ መካከል ፡ ክብሬንም ፡ ይናገራሉ ። የእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ቍርባናቸውን ፡ በጥሩ ፡ ዕቃ ፡ አድር
ገው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እንደሚያ
መጡ ፥ እንዲሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቍርባን ፡
ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ወንድሞቻችሁን ፡ ሁሉ ፥ በፈረ
ሶችና ፡ በሰረገሎች ፥ በአልጋዎችና ፡ በበቅሎች ፡
በጠያር ፡ ግመሎችም ፡ ላይ ፡ አድርገው ፥ ከአ
ሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ተቀደሰው ፡ ተራራዬ ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ያመጡአቸዋል ፥ ይላል ፡ እግዚ
፳፩ አብሔር ። ካህናትና ፡ሌዋውያን ፡ እንዲሆኑ ፡
ከእነርሱ ፡ እወስዳለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
፳፪ እኔ ፡ የምሠራቸው ፡ አዲስ ፡ ሰማይና ፡ አዲስ ፡
ምድር ፡ ከፊቴ ፡ ጸንተው ፡ እንደሚኖሩ ፥ እን
ዲሁ ፡ ዘራችሁና ፡ ስማችሁ ፡ ጸንተው ፡ ይኖ
፳፫ ራሉ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። እንዲህ ፡ ይሆ
ናል ፤ በየመባቻውና ፡ በየሰንበቱ ፡ ሥጋ ፡ ለባሽ ፡
ሁሉ ፡ በፊቴ ፡ ይሰግድ ፡ ዘንድ ፡ ዘወትር ፡ ይመ
፳፬ ጣል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ወጥተውም ፡
በእኔ ፡ ያመፁብኝን ፡ ሰዎች ፡ ሬሳቸውን ፡ ያያሉ ፤
ትላቸው ፡ አይሞትምና ፥ እሳታቸውም ፡ አይጠ
ፋምና ፤ ለሥጋ ፡ ለባሽም ፡ ሁሉ ፡ አስጸያፊ ፡
ነገር ፡ ይሆናሉ ።

# ትንቢተ ፡ ኤርምያስ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ በብንያም ፡ አገር ፡ በዓናቶት ፡ ከነበሩ ፡ ካህ
ናት ፡ የሆነ ፡ የኬልቅያስ ፡ ልጅ ፡ የኤርምያስ ፡
፪ ቃል ። በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በአሞጽ ፡ ልጅ ፡ በኢ
ዮስያስ ፡ ዘመን ፡ በመንግሥቱ ፡ በአሥራ ፡ ሦስ
ተኛው ፡ ዓመት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ መጣ
፫ ለት ። በይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡
በኢዮአቄም ፡ ዘመን ፥ እስከ ፡ ይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡
እስከ ፡ ኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ እስከ ፡ ሴዴቅያስ ፡
እስከ ፡ አሥራ ፡ አንደኛው ፡ ዓመት ፡ ፍጻሜ ፥
ኢየሩሳሌም ፡ እስከ ፡ ተማረከችበት ፡ እስከ ፡ አም
ስተኛው ፡ ወር ፡ ድረስ ፡ መጣ ።
፬ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፭ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— በሆድ ፡ ሳልሠራህ ፡ አው
ቄሃለሁ ፥ ከማኅፀንም ፡ ሳትወጣ ፡ቀድሼሃለሁ ፥
፮ ለአሕዛብም ፡ ነቢይ ፡ አድርጌሃለሁ ። እኔም ፡—
ወዮ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥ እነሆ ፥ ብላቴና ፡
ነኝና ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ አላውቅም ፡ አልሁ ።
፯ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡— ወደምስ
ድድህ ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ ትሄዳለህና ፥ የማዝዝህ
ንም ፡ ሁሉ ፡ ትናገራለህና ፡— ብላቴና ፡ ነኝ ፡
፰ አትበል ። እኔ ፡ አድንህ ፡ ዘንድ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡
ነኝና ፡ ከፊታቸው ፡ አትፍራ ፥ ይላል ፡ እግዚ

፱ አብሔር ። እግዚአብሔርም ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡
አፌን ፡ ዳሰሰ ፤ እግዚአብሔርም ፡— እነሆ ፤
፲ ቃሌን ፡ በአፍህ ፡ ውስጥ ፡ አኑሬአለሁ ፤ እነሆ ፤
ትነቅልና ፡ ታፈርስ ፡ ዘንድ ፤ ታጠፋና ፡ ትገለ
ብጥ ፡ ዘንድ ፤ ትሠራና ፡ ትተክል ፡ ዘንድ ፡ በአ
ሕዛብና ፡ በመንግሥታት ፡ ላይ ፡ ዛሬ ፡ አድርጌ
ሃለሁ ፡ አለኝ ።
፲፩ ደግሞ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡— ኤርም
ያስ ፡ ሆይ ፤ ምን ፡ ታያለህ ? እያለ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡
መጣ ። እኔም ፡— የለውዝ ፡ በትር ፡ አያለሁ ፡
፲፪ አልሁ ። እግዚአብሔርም ፡— እፈጽመው ፡
ዘንድ ፡ በቃሌ ፡ እተጋለሁና ፡ መልካም ፡ አይተ
ሃል ፡ አለኝ ።
፲፫ ሁለተኛም ፡ ጊዜ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡—
ምን ፡ ታያለህ ? እያለ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጣ ።
እኔም ፡— የሚፈላ ፡ አፍላል ፡ አያለሁ ፤ ፊቱም ፡
፲፬ ከሰሜን ፡ ወገን ፡ ነው ፡ አልሁ ። እግዚአብሔ
ርም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡— ከሰሜን ፡ ወገን ፡ ክፉ ፡
ነገር ፡ በምድሪቱ ፡ በተቀመጡ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡
፲፭ ይገለጣል ። እነሆ ፤ እኔ ፡ በሰሜን ፡ ያሉትን ፡
የመንግሥታትን ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ እጠራለሁ ፤
ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ እነርሱም ፡ ይመጣሉ ፡
እያንዳንዳቸውም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በር ፡ መግ
ቢያ ፡ በዙሪያዋ ፡ በቅጥርዋ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በይ
ሁዳም ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ዙፋናቸውን ፡
፲፮ ያስቀምጣሉ ። ስለ ፡ ክፋታቸውም ፡ ሁሉ ፤
እኔን ፡ ስለ ፡ ተዉ ፡ ለሌሎችም ፡ አማልክት ፡
ስላጠኑ ፡ ለእጃቸውም ፡ ሥራ ፡ ስለ ፡ ሰገዱ ፤
፲፯ ፍርዴን ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ እናገራለሁ ። አንተ ፡
ግን ፡ ወገብህን ፡ ታጠቅ ፤ ተነሥም ፤ ያዘዝሁህ
ንም ፡ ሁሉ ፡ ንገራቸው ፤ በፊታቸው ፡ እንዳላስ
፲፰ ፈራህ ፡ አትፍራቸው ። እነሆ ፤ በምድሪቱ ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ በይሁዳም ፡ ነገሥታት ፡ በአለቆች
ቍና ፡ በካህናትዋ ፡ ላይ ፡ በምድሪቱም ፡ ሕዝብ ፡
ላይ ፡ እንደ ፡ ተመሸገ ፡ ከተማ ፡ እንደ ፡ ብረትም ፡
ዓምድ ፡ እንደ ፡ ናስም ፡ ቅጥር ፡ ዛሬ ፡ አድርጌሃ
፲፱ ለሁ ። ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይዋጋሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡
አድንህ ፡ ዘንድ ፡ እኔ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነኝና ፡
ድል ፡ አይነሡህም ፤ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፪ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ሂድ ፤ በኢየሩሳሌም ፡
ጆሮ ፡ ጩኽ ፤ እንዲህም ፡ በል ፡— እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የብላቴንነትሽን ፡ ምሕ
ረት ፡ የታጨሽበትንም ፡ ፍቅር ፤ በምድረ ፡ በዳ ፡
ዘር ፡ ባልተዘራበት ፡ ምድር ፡ እንደ ፡ ተከተል
፫ ሽኝ ፡ አስቤአለሁ ። እስራኤል ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ ቅዱስ ፡ ነበረ ፤ የቡቃያውም ፡ በኵራት ፡
ነበረ ፤ የበሉት ፡ እንደ ፡ በደለኞች ፡ ይቈጠራሉ ፤
ክፉም ፡ ነገር ፡ ያገኛቸዋል ፤ ይላል ፡ እግዚአ
ብሔር ።
፬ የያዕቆብ ፡ ቤት ፡ የእስራኤልም ፡ ቤት ፡ ወገ
ኖች ፡ ሁሉ ፡ ሆይ ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
፭ ስሙ ። እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
አባቶቻችሁ ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ የራቁ ፤ ከንቱነት
ንም ፡ የተከተሉ ፤ ከንቱም ፡ የሆኑ ፡ ምን ፡ ክፋት ፡
፮ አግኝተውብኝ ፡ ነው ? እነርሱም ፡— ከግብጽ ፡
ምድር ፡ ያወጣን ፤ በምድረ ፡ በዳም ፡ በበድማ ፡
ጕድጓድም ፡ በለበት ፡ ምድር ፤ በውኃ ፡ ጥምና ፡
በሞት ፡ ጥላ ፡ ምድር ፤ ማንም ፡ በማያልፍበ
ትና ፡ ማንም ፡ በማይቀመጥበት ፡ ምድር ፡ የመ
ራን ፡ እግዚአብሔር ፡ ወዴት ፡ አለ ? አላሉም ።
፯ ፍሬዋንና ፡ በረከትዋንም ፡ ትበሉ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡
ፍሬያማ ፡ ምድር ፡ አገባኋችሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በገ
ባችሁ ፡ ጊዜ ፡ ምድሬን ፡ አረከሳችሁ ፤ ርስቴ
፰ ንም ፡ አጐሳቈላችሁ ። ካህናቱም ፡— እግዚአ
ብሔር ፡ ወዴት ፡ አለ ? አላሉም ፤ ባለ ፡ ኦሪቶ
ችም ፡ አላወቁኝም ፤ ገዢዎችም ፡ ዐመፁብኝ ፤
ነቢያትም ፡ በበኣል ፡ ትንቢት ፡ ተናገሩ ፤ የማይ
ረባንም ፡ ነገር ፡ ተከተሉ ።
፱ ስለዚህ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እከራከራለሁ ፤
ከልጆቻችሁም ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ እከራከራለሁ ።
፲ ወደ ፡ ኪቲም ፡ ደሴቶች ፡ እለፉና ፡ ተመልከቱ ፤
ወደ ፡ ቄዳርም ፡ ላኩና ፡ እጅግ ፡ መርምሩ ፤ እን
ደዚህም ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ሆኖ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እዩ ።
፲፩ በውኑ ፡ አማልክት ፡ ያልሆኑትን ፡ አማልክቱን ፡
የለወጣቸው ፡ አንድ ፡ ሕዝብ ፡ አለን ? ነገር ፡
ግን ፡ ሕዝቤ ፡ ክብሩን ፡ ለማይረባ ፡ ነገር ፡ ለወጠ ።
፲፪ ሰማያት ፡ ሆይ ፤ በዚህ ፡ ተደነቁ ፤ እጅግም ፡
ደንግጡና ፡ ተንቀጥቀጡ ፡ ይላል ፡ እግዚአብ
፲፫ ሔር ። ሕዝቤ ፡ ሁለቱን ፡ ክፉ ፡ ነገሮች ፡ አድር
ገዋልና ፤ እኔን ፡ የሕያውን ፡ ውኃ ፡ ምንጭ ፡ ትተ
ውኛል ፤ የተቀደዱትንም ፡ ጕድጓዶች ፤ ውኃ
ውን ፡ ይይዙ ፡ ዘንድ ፡ የማይችሉትን ፡ ጕድጓ
ዶች ፤ ለራሳቸው ፡ ቈፍረዋል ።
፲፬ በውኑ ፡ እስራኤል ፡ ባሪያ ፡ ነውን ? ወይስ ፡
የቤት ፡ ውላጅ ፡ ነውን ? ስለ ፡ ምን ፡ ብዝበዛ ፡
፲፭ ሆነ ? የአንበሳ ፡ ደቦሎች ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ አገሡ ፤
ድምፃቸውንም ፡ ሰጡ ፤ ምድሩንም ፡ ባድማ ፡
አደረጉ ፤ ከተሞቹም ፡ ተቃጠሉ ፡ የሚቀመጥ
፲፮ ባቸውም ፡ የለም ። የሜምፊስና ፡ የጣፍናስ ፡
፲፯ ልጆች ፡ አስነወሩሽ ፡ አላገጡብሽም ። ይህ ፡
ሁሉ ፡ የሆነብሽ ፡ እኔን ፡ ስለ ፡ ተውሽ ፡ አይደለ
፲፰ ምን ? ይላል ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክሽ ። አሁ
ንስ ፡ የሺሖርን ፡ ውኃ ፡ ትጠጪ ፡ ዘንድ ፡ በግ
ብጽ ፡ መንገድ ፡ ምን ፡ ጉዳይ ፡ አለሽ ? የኤፍራ
ጥስንም ፡ ውኃ ፡ ትጠጪ ፡ ዘንድ ፡ በአሦር ፡ መን
፲፱ ገድ ፡ ምን ፡ ጉዳይ ፡ አለሽ ? ክፋትሽ ፡ ይገሥጽ
ሻል ፡ ክዳትሽም ፡ ይዘልፍሻል ፤ አምላክሽንም ፡
እግዚአብሔርን ፡ የተውሽ ፡ እኔንም ፡ መፍራት ፡
የሌለብሽ ፡ ክፉና ፡ መራራ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
እወቂ ፤ ተመልከቺ ፤ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ።
፳ ከጥንት ፡ ጀምሬ ፡ ቀንበርሽን ፡ ሰብሬአለሁ ፡
እስራትሽንም ፡ ቈርጬለሁ ፤ አንቺም ፡— አላገ
ለግልም ፡ አልሽ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከፍ ፡ ባለው ፡
ኮረብታ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከለምለምም ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡

፳፩ በታች ፡ ለማመንዘር ፡ ተጋደምሽ ። እኔ ፡ የተ
መረጠች ፡ ወይን ፡ ፍጹምም ፡ እውነተኛ ፡ ዘር ፡
አድርጌ ፡ ተክዬሽ ፡ ነበር ፤ አንቺ ፡ ግን ፡ ክፉ ፡
የእንግዳ ፡ ወይን ፡ ግንድ ፡ ሆንሽ ፡ እንዴት ፡ ተለ
፳፪ ወጥሽብኝ ? በእንዶድ ፡ ብትታጠቢም ÷ ለራ
ስሽም ፡ ሳሙና ፡ ብታበዢ ÷ በእኔ ፡ ፊት ፡ በኃ
ጢአትሽ ፡ ረክሰሻል ፡ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
፳፫ ሔር ። አንቺስ ፡— አልረከስሁም ፡ በኣሊ.ም
ንም ፡ አልተከተልሁም ፡ እንዴት ፡ ትያለሽ ?
በቈላ ፡ ያለውን ፡ መንገድሽን ፡ ተመልከቺ ÷
ያደረግሽውንም ፡ እወቂ ፤ በመንገድም ፡ ላይ ፡
እንደ ፡ ተለቀቀች ፡ እንደ ፡ ፈጣን ፡ ግመል ፡ ሆን
፳፬ ሻል ፤ በምኞትዋ ፡ ነፋስን ፡ እንደምታሸትት ÷
በምድረ ፡ በዳ ፡ እንደ ፡ ለመደች ፡ እንደ ፡ ሜዳ ፡
አህያ ፡ ነሽ ፤ ከምኞትዋ ፡ የሚመልሳት ፡ ማን ፡
ነው ? የሚሹአት ፡ ሁሉ ፡ አይደክሙም ÷ በወ
፳፭ ራትዋ ፡ ያገኙአታል ። እግርሽን ፡ ከሽከራ ፡ መን
ገድ ፡ ጕሮሮሽንም ፡ ከውኃ ፡ ጥም ፡ ከልክዪ ፤
አንቺ ፡ ግን ፡— እጨክናለሁ ÷ እንግዶችን ፡ ወድ
ጀአለሁና ÷ እከተላቸዋለሁም ፡ አልሽ ።

፳፮ ሌባ ፡ በተያዘ ፡ ጊዜ ፡ እንደሚያፍር ፡ እን
ዲሁ ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ÷ እነርሱና ፡ ንጉሦቻ
ቸውም ፡ አለቆቻቸውም ፡ ካህናቶቻቸውም ፡
፳፯ ነቢያቶቻቸውም ፡ ያፍራሉ ። ግንዱን ፡— አንተ ፡
አባቴ ፡ ነህ ፤ ድንጋዩንም ፡— አንተ ፡ ወለድሽኝ ፡
ይላሉ ፤ ፊታቸውንም ፡ ሳይሆን ፡ ጀርባቸውን ፡
ሰጡኝ ÷ በመከራቸው ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡— ተነሥ
፳፰ ተህ ፡ አድነን ፡ ይላሉ ። ለአንተ ፡ የሠራሃቸው ፡
አማልክትህ ፡ ግን ፡ ወዴት ፡ ናቸው ? ይሁዳ ፡
ሆይ ÷ አማልክትህ ፡ እንደ ፡ ከተሞችህ ፡ ቍጥር ፡
እንዲሁ ፡ ናቸውና ፡ ይነሡ ፡ በመከራህም ፡ ጊዜ ፡
ያድኑህ ።

፳፱ ከእኔ ፡ ጋር ፡ የምትከራከሩ ፡ ለምንድር ፡ ነው ?
ሁላችሁ ፡ ዐምፃችሁብኛል ፡ ይላል ፡ እግዚአብ
፴ ሔር ። ልጆቻችሁን ፡ በከንቱ ፡ ቀሠፍኋቸዋ
ለሁ ፤ ተግሣጽን ፡ አልተቀበሉም ፤ ሰይፋችሁ ፡
እንደሚሰብር ፡ አንበሳ ፡ ነቢያቶቻችሁን ፡ በል
፴፩ ቶአል ። ትውልድ ፡ ሆይ ÷ የእግዚአብሔርን ፡
ቃል ፡ ተመልከቱ ። በውኑ ፡ ለእስራኤል ፡ ምድረ ፡
በዳ ፡ ወይስ ፡ የጨለመች ፡ ምድር ፡ ሆንሁበትን ?
ሕዝቤስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡— እኛ ፡ ፈርጥጠናል ፤
ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ አንመለስም ፡
፴፪ ይላል ? በውኑ ፡ ቆንጆ ፡ ጌጥዋን ፡ ወይስ ፡
ሙሽራ ፡ ዝርግፍ ፡ ጌጥዋን ፡ ትረሳለችን ? ሕዝቤ ፡
፴፫ ግን ፡ የማይቈጠር ፡ ወራት ፡ ረስቶኛል ። ፍቅ
ርን ፡ ለመሻት ፡ መንገድሽን ፡ እንዴት ፡ ታቀኛ
ለሽ ! ስለዚህ ፡ ለክፉዎች ፡ ሴቶች ፡ እንኳ ፡ መን
፴፬ ገድሽን ፡ አስተምረሻል ። በእጆችሽም ፡ የንጹ
ሐን ፡ ድሆች ፡ ደም ፡ ተገኝቶአል ፤ በእነዚህ ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ በግልጥ ፡ አገኘሁት ፡ እንጂ ፡ በስ
፴፭ ውር ፡ ፈልጌ ፡ አላገኘሁትም ። አንቺ ፡ ግን ፡—
ንጹሕ ፡ ነኝ ፤ በእውነት ፡ ቍጣው ፡ ከእኔ ፡ ተመ
ልሶአል ፡ አልሽ ። እነሆ ፡— ኃጢአት ፡ አልሠራ
፴፮ ሁም ፡ ብለሻልና ፡ በፍርድ ፡ እከስስሻለሁ ። መን
ገድሽን ፡ ትለውጪ ፡ ዘንድ ፡ ለምን ፡ እጅግ ፡
ትሮጫለሽ ? አሦር ፡ እንዳሳፈረሽ ፡ ግብጽ ፡ ያሳ
፴፯ ፍርሻል ። እግዚአብሔር ፡ የታመንሽባቸውን ፡
ጥሎአልና ÷ በእነርሱም ፡ አይከናወንልሽምና ፡
እጅሽን ፡ በራስሽ ፡ ላይ ፡ አድርገሽ ፡ ከዚያ ፡
ደግሞ ፡ ትወጫለሽ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ በሰው ፡ ዘንድ ፡— ሰው ፡ ሚስቱን ፡ ቢፈታ ÷
ከእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ሄዳ ፡ ሌላ ፡ ወንድ ፡ ብታገባ ÷
በውኑ ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ትመለሳለችን ?
ያች ፡ ሴት ፡ እጅግ ፡ የረከሰች ፡ አይደለችምን ?
ይባላል ። አንቺ ፡ ከብዙ ፡ ውሽሞች ፡ ጋር ፡ አመን
ዝረሻል ÷ ወደ ፡ እኔም ፡ ትመለሻለሽን ? ይላል ፡
፪ እግዚአብሔር ። ዓይንሽን ፡ አንሥተሽ ፡ ወደ ፡
ወናዎች ፡ ኮረብቶች ፡ ተመልከቺ ! ያልተጋደ
ምሽበት ፡ ስፍራ ፡ ወዴት ፡ አለ ? ዓረባዊ ፡ በም
ድረ ፡ በዳ ፡ እንደሚቀመጥ ፡ አንቺ ፡ በመንገድ ፡
ላይ ፡ ተቀምጠሽ ፡ ትጠብቂያቸው ፡ ነበር ፤ በግ
ልሙትናሽና ፡ በኃጢአትሽ ፡ ምድሪቱን ፡ አረ
፫ ከስሽ ። ስለዚህ ፡ ካፊያ ፡ ተከለከለ ÷ የኋለኛ
ውም ፡ ዝናብ ፡ ጠፋ ፤ የጋለሞታም ፡ ሴት ፡
ፊት ፡ ነበረብሽ ÷ ታፍሪም ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ ብለ
፬ ሻል ። አሁንም ፡— አንተ ፡ አባቴ ፡ ሆይ ÷ የብ
ላቴንነቴ ፡ ወዳጅ ፡ ነህ ፡ ብለሽ ፡ አልጮኽሽልኝ
፭ ምን ? ለዘላለም ፡ ይቈጣልን ? እስከ ፡ ፍጻሜስ ፡
ድረስ ፡ ይጠብቀዋልን ? እነሆ ÷ እንዲህ ፡ ብለሽ ፡
ተናገርሽ ÷ እንደ ፡ ተቻለሽም ፡ መጠን ፡ ክፉን ፡
ነገር ፡ አደረግሽ ።

፮ እግዚአብሔርም ፡ በንጉሡ ፡ በኢዮስያስ ፡
ዘመን ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡— ከዳተኛይቱ ፡ እስራ
ኤል ፡ ያደረገችውን ፡ አየህን ? ወደ ፡ ረዘመው ፡
ተራራ ፡ ሁሉ ፡ ከለመለመ ፡ ዛፍም ፡ ሁሉ ፡
፯ በታች ፡ ሄደች ፡ በዚያም ፡ ጋለሞተች ። ይህ
ንም ፡ ሁሉ ፡ ካደረገች ፡ በኋላ ፡— ወደ ፡ እኔ ፡
ትመለሳለች ፡ ብዬ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አልተመ
ለሰችም ፤ አታላይ ፡ እኅትዋም ፡ ይሁዳ ፡ አየች ።
፰ ከዳተኛይቱም ፡ እስራኤል ፡ ስላመነዘረች ፡ ስለ
ዚህ ፡ ፈትቻታለሁ ፡ የፍችዋንም ፡ ወረቀት ፡
ሰጥቻታለሁ ፤ አታላይ ፡ እኅትዋ ፡ ይሁዳ ፡
ግን ፡ እንዳልፈራች ፡ እርስዋም ፡ ደግሞ ፡
፱ ሄዳ ፡ እንደ ፡ ጋለሞተች ፡ አየሁ ። በግልሙት
ናዋም ፡ በመቅለልዋም ፡ ምድሪቱ ፡ ረከሰች ፤
እርስዋም ፡ ከድንጋይና ፡ ከግንድ ፡ ጋር ፡ አመነ
፲ ዘረች ። በዚህም ፡ ሁሉ ፡ አታላይቱ ፡ ይሁዳ ፡
በሐሰት ፡ እንጂ ፡ በፍጹም ፡ ልብዋ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡
አልተመለሰችም ።

፲፩ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡— ከአታ
ላይቱ ፡ ከይሁዳ ፡ ይልቅ ፡ ከዳተኛይቱ ፡ እስራ
፲፪ ኤል ፡ ጸደቀች ። ሂድና ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ወደ ፡
ሰሜን ፡ ተናገር ÷ እንዲህም ፡ በል ፡— ከዳተኛ
ይቱ ፡ እስራኤል ፡ ሆይ ÷ ተመለሽ ÷ ይላል ፡ እግ
ዚአብሔር ፤ መሐሪ ፡ ነኝና ÷ ለዘላለምም ፡ አል
ቈጣምና ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ፊቴን ፡ አላደርግም ÷

፲፫ ይላል፡እግዚአብሔር። በአምላክሽ፡በእግዚ
አብሔር፡ላይ፡እንዳመፅሽ፥መንገድሽንም፡
ከለመለመ፡ዛፍ፡ሁሉ፡በታች፡ለእንግዶች፡
እንደ፡ዘረጋሽ፥ቃሌንም፡እንዳልሰማሽ፡
ኃጢአትሽን፡ብቻ፡እወቂ፡ይላል፡እግዚአብ
፲፬ ሔር። ከዳተኞች፡ልጆች፡ሆይ፥እኔ፡ባላ
ችሁ፡ነኝና፡ተመለሱ፡ይላል፡እግዚአብሔር፤
አንዱንም፡ከአንዲት፡ከተማ፡ሁለቱንም፡
ከአንድ፡ወገን፡እወስዳችኋለሁ፥ወደ፡ጽዮ
፲፭ ንም፡አመጣችኋለሁ፤እንደ፡ልቤም፡በግ፡
ጠባቆችን፡እሰጣችኋለሁ፥በእውቀትና፡በማ
፲፮ ስተዋልም፡ይጠብቁአችኋል። በበዛችሁም፡
ጊዜ፡በምድርም፡ላይ፡በረባችሁ፡ጊዜ፥
ይላል፡እግዚአብሔር፥በዚያ፡ዘመን፡—የእግ
ዚአብሔር፡የቃል፡ኪዳኑ፡ታቦት፡ብለው፡ከእ
ንግዲህ፡ወዲህ፡አይጠሩም፤ልብ፡አያደርጉ
ትም፥አያስቡትምም፥አይሹትምም፥ከእንግ
፲፯ ዲህ፡ወዲህም፡አይደረግም። በዚያም፡ዘመን፡
ኢየሩሳሌምን፡የእግዚአብሔር፡ዙፋን፡ብለው፡
ይጠሩአታል፥አሕዛብም፡ሁሉ፡ወደ፡እር
ስዋ፡ይሰበሰባሉ፤ከእንግዲህም፡ወዲህ፡ክፉ
ውን፡እልከኛ፡ልባቸውን፡ተከትለው፡አይ
፲፰ ሄዱም። በዚያም፡ዘመን፡የይሁዳ፡ቤት፡
ወደ፡እስራኤል፡ቤት፡ይሄዳል፤በአንድም፡
ሆነው፡ከሰሜን፡ምድር፡ርስት፡አድርጌ፡ለአ
ባቶቻቸው፡ወደ፡ሰጠኋት፡ምድር፡ይመጣሉ።
፲፱ እኔ፡ግን፡—ከወንዶች፡ልጆች፡ጋር፡እን
ዴት፡አደርግሻለሁ? ያማረችውንስ፡ምድር፡
የከበረችውን፡የአሕዛብን፡ሠራዊት፡ርስት፡
እንዴት፡እሰጥሻለሁ? ብዬ፡ነበር። ደግሞ፡—
አባቴ፡ብለሽ፡ትጠሪኛለሽ፡እኔንም፡ከመከ
፳ ተል፡አትመለሽም፡ብዬ፡ነበር። የእስራኤል፡
ቤት፡ሆይ፥ሚስት፡ባልዋን፡እንደምታታ
ልል፡እንዲሁ፡አታለላችሁኝ፡ይላል፡እግዚአ
፳፩ ብሔር። የእስራኤል፡ልጆች፡መንገዳቸውን፡
አጣምመዋልና፥አምላካቸውንም፡እግዚአብ
ሔርን፡ረስተዋልና፡በወናዎች፡ከረብቶች፡ላይ፡
የልመናቸውና፡ልቅሶአቸው፡ድምፅ፡ተሰማ።
፳፪ ከዳተኞች፡ልጆች፡ሆይ፥ተመለሱ፥ከዳተ
ኛነታችሁንም፡እፈውሳለሁ። እነሆ፥አንተ፡
አምላካችን፡እግዚአብሔር፡ነህና፡ወደ፡አንተ፡
፳፫ እንመጣለን። በእውነት፡የከረብቶችና፡የተ
ራሮች፡ፍጅት፡ከንቱ፡ናት፤በእውነት፡የእ
ስራኤል፡መዳን፡በአምላካችን፡በእግዚአብ
፳፬ ሔር፡ዘንድ፡ነው። ነገር፡ግን፡ከትንሽነታ
ችን፡ጀምሮ፡የአባቶቻችን፡ድካም፥በጎቻቸ
ውንና፡ላሞቻቸውን፡ወንዶችና፡ሴቶች፡ልጆ
፳፭ ቻቸውንም፥እፍረት፡በልቶብናል። ከትን
ሽነታችን፡ጀምሮ፡እስከ፡ዛሬ፡ድረስ፡እኛና፡
አባቶቻችን፡በአምላካችን፡በእግዚአብሔር፡
ላይ፡ኃጢአት፡ሠርተናልና፥የአምላካችን
ንም፡የእግዚአብሔርን፡ቃል፡አልሰማንምና፡
በእፍረታችን፡እንጋደም፥ውርደታችንም፡
ይከድነን።

## ምዕራፍ፡ ፬ ።

፩ እስራኤል፡ሆይ፥ብትመለስ፥ወደ፡እኔ፡
ተመለስ፥ይላል፡እግዚአብሔር፤ርኵሰትህ
ንም፡ከፊቴ፡ብታስወግድ፥ብትናወጥም፥
፪ ሕያው፡እግዚአብሔርን! ብለህም፡በእውነ
ትና፡በቅንነት፡በጽድቅም፡ብትምል፥አሕ
ዛብ፡በእርሱ፡ይበረከላሉ፡በእርሱም፡ይመካሉ።
፫ እግዚአብሔር፡ለይሁዳና፡ለኢየሩሳሌም፡
ሰዎች፡እንዲህ፡ይላልና፡—ጥጋቱን፡እርሹ፡
፬ እረሱ፡በእሾህም፡ላይ፡አትዝሩ። እናንተም፡
የይሁዳ፡ሰዎች፡በኢየሩሳሌምም፡የምትኖሩ፡
ሆይ፥ስለ፡ሥራችሁ፡ክፋት፡ቍጣዬ፡እንደ፡
እሳት፡እንዳይወጣ፡የሚያጠፋውም፡ሳይኖር፡
እንዳያቃጥል፥ለእግዚአብሔር፡ተገረዙ፥የል
ባችሁንም፡ሸለፈት፡አስወግዱ።
፭ በይሁዳ፡ዘንድ፡ተናገሩ፡በኢየሩሳሌምም፡
ላይ፡አውሩና፡—በአገሪቱ፡ላይ፡መለከት፡ንፉ፡
በሉ፤ጮኻችሁም፡—ሁላችሁ፡ተሰብሰቡ፡
ወደ፡ተመሸጉትም፡ከተሞች፡እንግባ፡በሉ።
፮ ከሰሜን፡ክፉ፡ነገርንና፡ጽኑ፡ጥፋትን፡አመ
ጣለሁና፡ወደ፡ጽዮን፡ዓላማን፡አንሡ፤ሽሹ፥
፯ አትዘግዩ። አንበሳ፡ከጭፍቅ፡ዱር፡ወጥቶአል፥
አሕዛብንም፡የሚዘርፍ፡ተነሥቶአል፤ምድር
ሽን፡ባድማ፡ያደርግ፡ዘንድ፡ከስፍራው፡ወጥ
ቶአል፥ከተሞችሽም፡ሰው፡የሌለባቸው፡ፍር
፰ ስራሾች፡ይሆናሉ። የእግዚአብሔር፡ጽኑ፡
ቍጣ፡ከእኛ፡ዘንድ፡አልተመለሰምና፡ማቅ፡
፱ ልበሱ፥አልቅሱም፡ዋይም፡በሉ። በዚያም፡
ቀን፥ይላል፡እግዚአብሔር፥የንጉሡና፡የመ
ኳንንቱ፡ልብ፡ይጠፋል፥ካህናቱም፡ይደነ
ቃሉ፡ነቢያቱም፡ይደነግጣሉ።
፲ እኔም፡—ጌታ፡እግዚአብሔር፡ሆይ፥ወዮ፥
አንተ፡ሰይፍ፡እስከ፡ነፍስ፡ድረስ፡በደረሰ፡
ጊዜ፡—ሰላም፡ይሆንላችኋል፡ብለህ፡ይህን፡
ሕዝብና፡ኢየሩሳሌምን፡እጅግ፡አታለልህ፡
አልሁ።
፲፩ በዚያ፡ጊዜ፡ለዚህ፡ሕዝብና፡ለኢየሩሳሌም፡—
ለማበጠር፡ወይም፡ለማጥራት፡ሳይሆን፡የሚ
ያቃጥል፡ነፋስ፡በምድረ፡በዳ፡ካሉ፡ከወና
ዎች፡ከረብቶች፡ወደ፡ወገኔ፡ሴት፡ልጅ፡
፲፪ ይመጣል፤ስለ፡እኔ፡ጽኑ፡የሆነ፡ነፋስ፡ከእ
ነዚህ፡ይመጣል፡ይባላል። አሁንም፡እኔ፡
ደግሞ፡ፍርዴን፡በእነርሱ፡ላይ፡እናገራለሁ።
፲፫ እነሆ፥እንደ፡ደመና፡ይወጣል፥ሰረገሎቹም፡
እንደ፡ዐውሎ፡ነፋስ፤ፈረሶቹም፡ከንስር፡
ይልቅ፡ፈጣኖች፡ናቸው። ጠፍተናልና፡ወዮ
፲፬ ልን። ኢየሩሳሌም፡ሆይ፥ትድኚ፡ዘንድ፡
ልብሽን፡ከክፉ፡ነገር፡እጠቢ። ክፉ፡አሳብ፡
፲፭ የሚኖርብሽ፡እስከ፡መቼ፡ድረስ፡ነው? የተ
ናጋሪ፡ድምፅ፡ከዳን፡ዘንድ፡ይናገራልና፥
ከኤፍሬምም፡ከረብቶች፡መከራን፡ያወራ
፲፮ ልና። ለአሕዛብ፡አሰሙና፡—እነሆ፥ጠባቂ
ዎች፡ከሩቅ፡አገር፡ይመጣሉ፤በይሁዳም፡

ከተሞች ፡ ላይ ፡ ይጮኻሉ ፡ ብላችሁ ፡ በኢየሩ
፲፯፤ ሳሌም ፡ ላይ ፡ አውሩ ። በእኔ ፡ ላይ ፡ ዓመፀኛ ፡
ሆናለችና ፡ በዙሪያዋ ፡ ከብበው ፡ እንደ ፡ እርሻ ፡
ጠባቂዎች ፡ ሆነውባታል ÷ ይላል ፡ እግዚአብ
፲፰፤ ሔር ። መንገድሽና ፡ ሥራሽ ፡ ይህን ፡ አድር
ጎብሻል ፤ ይህ ፡ ክፋትሽ ፡ መራር ፡ ነው ÷ ወደ ፡
ልብሽም ፡ ደርሶአል ።

፲፱፤ አንጀቴ ! አንጀቴ ! ልቤ ፡ በጣም ፡ ታምሞ
አል ÷ በውስጤም ፡ ልቤ ፡ ታውኮብኛል ፤ ነፍሴ ፡
ሆይ ÷ የመለከትን ፡ ድምፅና ፡ የሰልፍን ፡
ውካታ ፡ ሰምተሻልና ፡ ዝም ፡ እል ፡ ዘንድ ፡
፳፤ አልችልም ። መከራ ፡ በመከራ ፡ ላይ ፡ ተጠር
ቶአል ፤ ምድርም ፡ ሁሉ ፡ ተበዝብዛለችና ፤ በድ
ንገትም ፡ ድንኳኔ ፡ በቅጽበት ፡ ዓይንም ፡ መጋ
፳፩፤ ረጃዎቼ ፡ ጠፉ ። ዓላማውን ፡ የምመለከት ÷
የመለከቱንስ ፡ ድምፅ ፡ የምሰማ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡
፳፪፤ ነው ? ሕዝቤ ፡ ሰንፈዋልና ፡ አላወቁኝም ፤ ሰነ
ፎች ፡ ልጆች ፡ ናቸው ÷ ማስተዋልም ፡ የላቸ
ውም ፤ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ለማድረግ ፡ ብልሃተኞች ፡
ናቸው ÷ በጎ ፡ ነገርን ፡ ማድረግ ፡ ግን ፡ አያውቁም ።

፳፫፤ ምድሪቱን ፡ አየሁ ÷ እነሆም ÷ ባዶ ፡ ነበረች ፡
አንዳችም ፡ አልነበረባትም ፤ ሰማያትንም ፡
፳፬፤ አየሁ ÷ ብርሃንም ፡ አልነበረባቸውም ። ተራሮ
ችን ፡ አየሁ ÷ እነሆም ÷ ተንቀጠቀጡ ÷ ኮረብ
፳፭፤ ቶችም ፡ ሁሉ ፡ ተናወጡ ። አየሁ ÷ እነሆም ÷
ሰው ፡ አልነበረም ÷ የሰማይም ፡ ወፎች ፡ ሁሉ ፡
፳፮፤ ሸሽተው ፡ ነበር ። አየሁ ÷ እነሆም ÷ ፍሬያማ ፡
እርሻ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሆነች ÷ ከተሞችም ፡ ሁሉ ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ከጽኑ ፡ ቍጣው ፡ የተ
ነሣ ፡ ፈርሰው ፡ ነበር ።

፳፯፤ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ምድር ፡
ሁሉ ፡ ባድማ ፡ ትሆናለች ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ፈጽሜ ፡
፳፰፤ አላጠፋትም ። ስለዚህ ፡ ምድር ፡ ታለቅሳለች ÷
በላይም ፡ ሰማይ ፡ ይጠቍራል ፤ ተናግሬአለሁና ÷
አስቤአለሁም ፤ አልጸጸትም ፡ ከእርሱም ፡ አል
፳፱፤ መለስም ። ከፈረሰኞችና ፡ ከቀስተኞች ፡ ድምፅ ፡
የተነሣ ፡ ከተማ ፡ ሁሉ ፡ ሸሸታለች ፤ ወደ ፡ ችፍግ ፡
ዱርም ፡ ይገባሉ ፡ በቋጥኝ ፡ ላይም ፡ ይወጣሉ ፤
ከተማ ፡ ሁሉ ፡ ተለቅቃለች ፡ የሚቀመጥባትም ፡
፴፤ ሰው ፡ የለም ። አንቺም ፡ የተበዘበዝሽ ፡ ሆይ ÷
ምን ፡ ታደርጊአለሽ ? ቀይ ፡ በለበስሽ ፡ ጊዜ ÷ በወ
ርቅ ፡ አንባርም ፡ ባጌጥሽ ፡ ጊዜ ÷ ዓይንሽንም ፡
በኵል ፡ በተኳልሽ ፡ ጊዜ ÷ በከንቱ ፡ ታጌጫ
ለሽ ፤ ውሽሞችሽ ፡ አቃለሉሽ ÷ ነፍስሽን ፡ ይሹ
፴፩፤ አታል ። እንደምታምጥ ፡ የበኵርዋንም ፡ እን
ደምትወልድ ፡ ሴት ፡ ድምፅ ፡ ሰምቻለሁና ፤ የጽ
ዮን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ድምፅ ፡ በድካም ፡ ይሰልላል ÷
እጆችዋንም ፡ ትዘረጋለችና ፡— ተገድለው ፡ ከሞ
ቱት ፡ የተነሣ ፡ ነፍሴ ፡ ዝላለችና ፡ ወዮልኝ !
አለች ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩፤ በኢየሩሳሌም ፡ መንገድ ፡ እየተመላለሳችሁ ፡
ሩጡ ÷ ተመልከቱም ÷ እወቁም ÷ በአደባባይ
ዋም ፡ ፈልጉ ፤ ፍርድን ፡ የሚያደርገውን ፡ እው
ነትንም ፡ የሚሻውን ፡ ሰው ፡ ታገኙ ፡ እንደ ፡
፪፤ ሆነ ፡ ይቅር ፡ እላታለሁ ። እነርሱም ፡— ሕያው ፡
እግዚአብሔርን ! ቢሉ ፡ የሚምሉት ፡ በሐሰት ፡
፫፤ ነው ። አቤቱ ÷ ዓይንህ ፡ እውነትን ፡ የምትመ
ለከት ፡ አይደለችምን ? አንተ ፡ ቀሥፈሃቸዋል ፡
ነገር ፡ ግን ፡ አላዘኑም ÷ ቀጥቅጠሃቸውማል ፡
ነገር ፡ ግን ፡ ተግሣጽን ፡ እንቢ ፡ አሉ ፤ ፊታቸ
ውን ፡ ከድንጋይ ፡ ይልቅ ፡ አጠንክረዋል ፤ ይመ
ለሱ ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ አሉ ።

፬፤ እኔም ፡— የእግዚአብሔርን ፡ መንገድና ፡ የአ
ምላካቸውን ፡ ሕግ ፡ አላወቁምና ፡ እነዚህ ፡ በእ
፭፤ ውነት ፡ ድሆችና ፡ ሰነፎች ፡ ናቸው ፤ ወደ ፡
ታላላቆቹ ፡ እሄዳለሁ ፡ እናገራቸውማለሁ ፤ የእ
ግዚአብሔርን ፡ መንገድና ፡ የአምላካቸውን ፡
ሕግ ፡ ያውቃሉና ፡ አልሁ ። እነዚህ ፡ ግን ፡ ቀን
በሩን ፡ በአንድነት ፡ ሰብረዋል ÷ እስራቱንም ፡
፮፤ ቈርጠዋል ። ስለዚህ ፡ ኃጢአታቸው ፡ በዝቶ
አልና ÷ የክዳታቸውም ፡ ብዛት ፡ ጸንቶአልና ፡
ስለዚህ ፡ አንበሳ ፡ ከዱር ፡ ወጥቶ ፡ ይሰብራቸ
ዋል ÷ የበረሀም ፡ ተኵላ ፡ ያጠፋቸዋል ÷ ነብ
ርም ፡ በከተሞቻቸው ፡ ላይ ፡ ይተጋል ÷ ከዚ
ያም ፡ የሚወጣ ፡ ሁሉ ፡ ይነጠቃል ።

፯፤ በእነዚህ ፡ ነገሮች ፡ ይቅር ፡ የምልሽ ፡ እን
ዴት ፡ አድርጌ ፡ ነው ? ልጆችሽ ፡ ትተውኛል ፡
አማልክትም ፡ ባልሆኑ ፡ ምለዋል ፤ ካጠገብኋ
ቸውም ፡ በኋላ ፡ አመነዘሩ ፡ በጋለሞቶቹም ፡
፰፤ ቤት ፡ ተሰበሰቡ ። እንደ ፡ ተቀለቡ ፡ ፈረሶች ፡
ሆኑ ፤ እያንዳንዳቸውም ፡ ከባልንጀሮቻቸው ፡
፱፤ ሚስቶች ፡ ኋላ ፡ አሽካኩ ። በውኑ ፡ ስለ ፡ እነ
ዚህ ፡ ነገሮች ፡ አልቀሥፍምን ? ይላል ፡ እግዚ
አብሔር ፤ ነፍሴስ ፡ እንደዚህ ፡ ባለ ፡ ሕዝብ ፡
ላይ ፡ አትበቀልምን ?

፲፤ ወደ ፡ ቅጥርዋ ፡ ወጥታችሁ ፡ አፍርሱ ÷ ነገር ፡
ግን ፡ ፈጽማችሁ ፡ አታጥፉ ፤ ለእግዚአብሔር ፡
፲፩፤ አይደሉምና ፡ ቅርንጫፍዋን ፡ ውሰዱ ። የእስ
ራኤል ፡ ቤትና ፡ የይሁዳ ፡ ቤት ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡
እጅግ ፡ ወንጅለዋል ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
፲፪፤ እነርሱም ፡— እርሱ ፡ አይደለም ÷ ክፉ ፡ ነገርም ፡
አይመጣብንም ፡ ሰይፍንና ፡ ራብንም ፡ አናይም ፤
፲፫፤ ነቢያትም ፡ ነፋስ ፡ ይሆናሉ ÷ የእግዚአብሔ
ርም ፡ ቃል ፡ በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ የለም ÷ እንዲ
ህም ፡ ይደረግባቸዋል ፡ ብለው ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ ክደዋል ።

፲፬፤ ስለዚህም ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— በዚህ ፡ ቃል ፡ ተናግራችኋ
ልና ፡ እነሆ ÷ በአፍህ ፡ ውስጥ ፡ ቃሌን ፡ እሳት ፡
ይህንም ፡ ሕዝብ ፡ እንጨት ፡ አደርጋለሁ ÷
፲፭፤ ትበላቸውማለች ። የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷
እነሆ ÷ ሕዝብን ፡ ከሩቅ ፡ አመጣባችኋለሁ ÷
ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ኃያል ፡ ጥንታዊ ፡
ሕዝብ ፡ ነው ÷ ቋንቋቸውንም ፡ የማታውቀው ፡
የሚናገሩትንም ፡ የማታስተውለው ፡ ሕዝብ ፡
፲፮፤ ነው ። የፍላጻቸውም ፡ ሰገባ ፡ እንደ ፡ ተከፈተ ፡

መቃብር፡ነው፤ሁሉም፡ኃያላን፡ናቸው።
፲፯፡ መከርህንና፡እንጀራህን፡ይበላሉ፤ወንዶችና፡
ሴቶች፡ልጆችህንም፡ይበሉአቸዋል፤በጎችህ
ንና፡ላሞችህንም፡ይበላሉ፤ወይንህንና፡በለ
ስህንም፡ይበላሉ፤የምትታመናቸውን፡የተ
መሸጉ፡ከተሞችን፡በሰይፍ፡ይደበድባሉ።
፲፰፡ ነገር፡ግን፡በዚያ፡ዘመን፤ይላል፡እግዚአብ
ሔር፤ፈጽሜ፡አላጠፋችሁም።
፲፱፡ እንዲህም፡ይሆናል፤እናንተ፡— አምላካ
ችን፡እግዚአብሔር፡ይህን፡ነገር፡ሁሉ፡ስለ፡
ምን፡አደረገብን? ብትሉ፤አንተ፡— እንደ፡
ተዋችሁኝ፡በአገራችሁም፡ሌሎችን፡አማል
ክት፡እንዳመለካችሁ፤እንዲሁ፡ለእናንተ፡
ባልሆነ፡አገር፡ለሌሎች፡ሰዎች፡ትገዛላችሁ፡
ትላቸዋለህ።
፳፡ ይህን፡በያዕቆብ፡ቤት፡አውሩ፤በይሁዳም፡
፳፩፡ አሰሙ፡— እናንተ፡ሰነፎች፡ልበ፡ቢሶች፤
ዓይን፡እያላችሁ፡የማታዩ፤ጆሮም፡እያላችሁ፡
የማትሰሙ፡ሕዝብ፡ሆይ፤ይህን፡ስሙ።
፳፪፡ በውኑ፡እኔን፡አትፈሩምን? ከፊቴስ፡አትደነ
ግጡምን? ይላል፡እግዚአብሔር፤እንዳያልፍ፡
አሸዋን፡በዘላለም፡ትእዛዝ፡ለባሕር፡ዳርቻ፡
አድርጌአለሁ፤ሞገዱም፡ቢናወጥ፡አያሸን
፳፫፡ ፍም፤ቢጮኽም፡አያልፍበትም። ለዚህ፡
ሕዝብ፡ግን፡የሸፈተና፡ያመፀ፡ልብ፡አላቸው፤
፳፬፡ ዐምፀዋል፡ሄደውማል። በልባቸውም፡— የፊ
ተኛውንና፡የኋለኛውን፡ዝናብ፡በጊዜው፡
የሚሰጠውን፤ለመከርም፡የተመደቡትን፡
ወራት፡የሚጠብቅልንን፡አምላካችንን፡እግ
፳፭፡ ዚአብሔርን፡እንፍራ፡አላሉም። በደላችሁ፡
እነዚህን፡አስቀርታለች፤ኃጢአታችሁም፡
፳፮፡ መልካምን፡ነገር፡ከለከለቻችሁ። በሕዝቤ፡
መካከል፡ክፉዎች፡ሰዎች፡ተገኝተዋል፤እንደ፡
አጥማጆችም፡ያደባሉ፤ወጥመድንም፡ይዘረ
፳፯፡ ጋሉ፡ሰዎችንም፡ያጠምዳሉ። ቀፎ፡ወፎ
ችን፡እንደሚሞላ፤እንዲሁ፡ቤታቸው፡ሽን
ገላን፡ሞልታለች፤እንዲሁም፡ከብረዋል፡ባለ
፳፰፡ ጠጎችም፡ሆነዋል። ወፍረዋል፡ሰብተውማል፤
ክፉታቸውንም፡ያለ፡ልክ፡አብዝተዋል፤
የድሀ፡አደጎች፡ነገር፡መልካም፡እንዲሆን፡አል
ተምዋገቱላቸውም፤የችግረኞችንም፡ፍርድ፡
፳፱፡ አልፈረዱላቸውም። በውኑ፡ስለ፡እነዚህ፡ነገ
ሮች፡አልቀሥፍምን? ይላል፡እግዚአብሔር፤
ነፍሴስ፡እንደዚህ፡ባለ፡ሕዝብ፡ላይ፡አትበ
ቀልምን?
፴፡ የምታስደንቅና፡የምታስደነግጥ፡ነገር፡
፴፩፡ በምድር፡ላይ፡ሆናለች፤ነቢያት፡በሐሰት፡
ትንቢት፡ይናገራሉ፤ካህናትም፡በእነዚህ፡
እጅ፡ይገዛሉ፤ሕዝቤም፡እንዲህ፡ያለውን፡
ነገር፡ይወድዳሉ፤በፍጻሜውስ፡ምን፡ታደር
ጋላችሁ?

## ምዕራፍ፡፮።

፩፡ እናንተ፡የብንያም፡ልጆች፤ክፉ፡ነገር፡
ታላቅም፡ጥፋት፡ከሰሜን፡ይጐበኛልና፡ከኢ
የሩሳሌም፡ውስጥ፡ሽሹ፤በቴቁሔ፡መለከቱን፡
ንፉ፤በቤትሐካሪም፡ላይ፡ምልክት፡አንሡ።
፪፡ የተዋበችውንና፡የተሰባቀለችውን፡የጽዮንን፡
፫፡ ልጅ፡አጐሰቍላለሁ። እረኞችና፡መንጎቻ
ቸው፡ወደ፡እርስዋ፡ይመጣሉ፤በዙሪያዋም፡
ድንኳኖቻቸውን፡ይተክሉባታል፤እያንዳን
ዱም፡በስፍራው፡መንጋውን፡ያሰማራል።
፬፡ በእርስዋ፡ላይ፡ሰልፍ፡አዘጋጁ፤ተነሡ፤በቀ
ትርም፡እንውጣ። ቀኑ፡መሽቶአልና፤የማታ
፭፡ ውም፡ጥላ፡ረዝሞአልና፡ወዮልን። ተነሡ፡
በሌሊትም፡እንውጣ፤አዳራሾችዋንም፡እና
፮፡ ፍርስ። የሠራዊት፡ጌታ፡እግዚአብሔር፡እን
ዲህ፡ይላልና፡— ዛፎችዋን፡ቍረጡ፤በኢየ
ሩሳሌምም፡ላይ፡አፈርን፡ደልድሉ፤ይህች፡
ከተማ፡የምትቀሥፍ፡ናት፤መካከልዋ፡ሁሉ፡
፯፡ ግፍ፡ብቻ፡ነው። በጕድጓድ፡ውኃ፡እን
ደሚፈልቅ፤እንዲሁ፡ክፋትዋ፡ከእርስዋ፡
ዘንድ፡ይፈልቃል፤ግፍና፡ቅሚያ፡በእር
ስዋ፡ዘንድ፡ይሰማል፤ደዌና፡ቍስልም፡
፰፡ ሁልጊዜ፡በፊቴ፡አለ። ኢየሩሳሌም፡ሆይ፤
ነፍሴ፡ከአንቺ፡እንዳትለይ፤አንቺንም፡ባድ
ማና፡ወና፡እንዳላደርግሽ፤ተግሣጽን፡ተቀ
በዪ።
፱፡ እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— ሰው፡
ወይኑን፡እንደሚቃርም፤እንዲሁ፡ከእስራ
ኤል፡የቀሩትን፡ፈጽሞ፡ይቃርሙአቸዋል፤እጅ
ህንም፡እንደ፡ለቃሚ፡ወደ፡እንቅብ፡ዘርጋ።
፲፡ ይሰሙኝስ፡ዘንድ፡ለማን፡እናገራለሁ? ለማ
ንስ፡አስጠነቅቃለሁ? እነሆ፤ጆሮአቸው፡ያል
ተገረዘች፡ናት፡ለመስማትም፡አይችሉም፤
እነሆ፤የእግዚአብሔር፡ቃል፡ለስድብ፡ሆኖ
፲፩፡ ባቸዋል፤ደስም፡አያሰኛቸውም። ስለዚህ፡በእ
ግዚአብሔር፡ቍጣ፡ተሞልቻለሁ፤ከመታ
ገሥ፡ደክሜአለሁ፤በሜዳ፡በሕፃናት፡ላይ፡
በጕልማሶችም፡ጉባዔ፡ላይ፡በአንድነት፡አፍ
ስሰው፤ባል፡ከሚስቱ፡ጋር፡ሽማግሌውም፡
፲፪፡ ከጎበዙ፡ጋር፡ይያያዛልና። እጄን፡በምድር፡
በሚኖሩ፡ላይ፡እዘረጋለሁና፡ቤቶቻቸው፡እር
ሻዎቻቸውም፡ሴቶቻቸውም፡በአንድነት፡
ለሌሎች፡ይሆናሉ፤ይላል፡እግዚአብሔር።
፲፫፡ ከታናሹ፡ጀምሮ፡እስከ፡ታላቁ፡ድረስ፡ሁሉ፡
ስስትን፡ያስባሉና፤ከነቢዩም፡ጀምሮ፡እስከ፡
ካህኑ፡ድረስ፡ሁሉ፡በተንኰል፡ያደርጋሉና።
፲፬፡ የሕዝቤንም፡ስብራት፡በጥቂቱ፡ይፈውሳሉ፤
ሰላም፡ሳይሆን፡— ሰላም፡ሰላም፡ይላሉ።
፲፭፡ ርኩስን፡ነገር፡ስለ፡ሠሩ፡አፍረዋልን? ምንም፡
አላፈሩም፤እፍረትንም፡አላወቁም፤ስለዚህ፡

ከሚወድቁ፡ጋር፡ይወድቃሉ፤በጐበኘኋቸው፡ ጊዜ፡ይዋረዳሉ÷ይላል፡እግዚአብሔር።

፲፮፤ እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— በመንገድ፡ላይ፡ቁሙ፡ተመልከቱም÷የቀደመችውንም፡መንገድ፡ጠይቁ፤መልካሚቱ፡መንገድ፡ወዴት፡እንደ፡ሆነች፡እወቁ÷በእርስዋም፡ላይ፡ሂዱ÷ለነፍሳችሁም፡ዕረፍት፡ታገኛላችሁ፤እነርሱ፡ግን፡— አንሄድባትም፡አሉ።
፲፯፤ እኔም፡— የመለከቱን፡ድምፅ፡አድምጡ፡ብዬ፡ጠባቆችን፡ሾምሁባችሁ፤እነርሱ፡ግን፡— አናደምጥም፡አሉ።
፲፰፤ አሕዛብ፡ሆይ÷ስለዚህ፡ስሙ፤ማኅበር፡ሆይ÷እነዚያ፡የሚያገኛቸውን፡እወቁ።
፲፱፤ ምድር፡ሆይ÷ስሚ፤እነሆ÷ቃሌን፡ስላልሰሙ፡ሕጌንም፡ስለ፡ጣሉ÷በዚህ፡ሕዝብ፡ላይ፡የአሳባቸውን፡ፍሬ÷ክፉን፡ነገር፡አመጣባቸዋለሁ።
፳፤ ስለ፡ምንስ፡ከሳባ፡ዕጣንን÷ከሩቅም፡አገር፡ቀረፋን፡ታቀርቡልኛላችሁ? የሚቃጠለውን፡መሥዋዕታችሁን፡አልቀበለውም፡ሌላ፡መሥዋዕታችሁም፡ደስ፡አያሰኘኝም።
፳፩፤ ስለዚህ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— እነሆ÷ከዚህ፡ሕዝብ፡ፊት፡ዕንቅፋቶችን፡አደርጋለሁ፤አባቶችና፡ልጆች፡በአንድነት፡ይሰናከሉባቸዋል÷ጎረቤትና፡ባልንጀራም፡ይጠፋሉ።
፳፪፤ እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— እነሆ÷ሕዝብ፡ከሰሜን፡አገር፡ይመጣል÷ታላቅ፡ሕዝብም፡ከምድር፡ዳርቻ፡ይነሣል።
፳፫፤ ቀስትንና፡ጦርን፡ይይዛሉ፤ጨካኞች፡ናቸው÷ምሕረትም፡አያደርጉም፤ድምፃቸው፡እንደ፡ባሕር፡ይተምማል÷በፈረሶችም፡ላይ፡ይቀመጣሉ፤የጽዮን፡ሴት፡ልጅ፡ሆይ÷ለሰልፍ፡እንደ፡ተዘጋጀ፡ሰው፡እያንዳንዳቸው፡በአንቺ፡ላይ፡ተሰለፉ።
፳፬፤ ወሬውን፡ሰምተናል÷እጃችን፡ደከማለች፤ምጥ፡ወላድን፡ሴት፡እንደሚይዛት፡ጭንቀት፡ይዞናል።
፳፭፤ የጠላት፡ሰይፍና፡ድንጋጤ፡ከብበዋችኋልና፡ወደ፡ሜዳ፡አትውጡ፡በመንገድም፡ላይ፡አትሂዱ።
፳፮፤ የሕዝቤ፡ልጅ፡ሆይ÷ማቅ፡ልበሺ፡በአመድም፡ውስጥ፡ተንከባለዪ፤አጥፊ፡በላያችን፡በድንገት፡ይመጣብናልና፡ለአንድያ፡ልጅ፡እንደሚደረግ፡ልቅሶ÷መራራ፡ልቅሶ፡አልቅሺ።
፳፯፤ መንገዳቸውን፡እንድታውቅና፡እንድትፈትን፡በሕዝቤ፡መካከል፡ፈታኝ፡አድርጌሃለሁ።
፳፰፤ እነርሱ፡ሁሉ፡እጅግ፡ዓመፀኞች፡ናቸው፤በጠማማነት፡ይሄዳሉ፤ናስና፡ብረት፡ናቸው፤ሁሉ፡ርኵሰትን፡ያደርጋሉ።
፳፱፤ ወናፉ፡አናፋ፡እርሳሱም፡በእሳት፡ቀለጠ፤አንጥረኛውም፡መልሶ፡በከንቱ፡ያቀልጠዋል፤ኃጢአተኞች፡አልተወገዱም።
፴፤ እግዚአብሔር፡ጥሎአቸዋልና፡የተጣለ፡ብር፡ብለው፡ይጠሩአቸዋል።

ምዕራፍ፡፯።

፩፤ ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ወደ፡ኤርምያስ፡የመጣ፡ቃል፡ይህ፡ነው።
፪፤ በእግዚአብሔር፡ቤት፡በር፡ቁም÷ይህንም፡ቃል፡እንዲህ፡ብለህ፡ተናገር፡— እግዚአብሔርን፡ልታመልኩ፡በእነዚህ፡በሮች፡የምትገቡ፡ከይሁዳ፡ያላችሁ፡ሁሉ፡የእግዚአብሔርን፡ቃል፡ስሙ።
፫፤ የእስራኤል፡አምላክ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— መንገዳችሁንና፡ሥራችሁን፡አሳምሩ፡በዚህም፡ስፍራ፡አሳድራችኋለሁ።
፬፤ የእግዚአብሔር፡መቅደስ÷የእግዚአብሔር፡መቅደስ÷የእግዚአብሔር፡መቅደስ፡ይህ፡ነው፡እያላችሁ፡በሐሰት፡ቃል፡አትታመኑ።
፭፤ መንገዳችሁንና፡ሥራችሁን፡ፈጽማችሁ፡ብታሳምሩ÷በሰውና፡በጎረቤቱ፡መካከል፡ቅን፡ፍርድ፡ብትፈርዱ÷
፮፤ መጻተኛውንና፡ድሀ፡አደጉን፡መበለቲቱንም፡ባትገፉ÷በዚህም፡ስፍራ፡ንጹሕ፡ደምን፡ባታፈስሱ÷ክፉም፡ሊሆንባችሁ፡እንግዶችን፡አማልክት፡ባትከተሉ÷
፯፤ ከዘላለም፡እስከ፡ዘላለም፡ለአባቶቻችሁ፡በሰጠኋቸው፡ምድር፡በዚህ፡ስፍራ፡አሳድራችኋለሁ።
፰፤ እነሆ÷በማትረቡበት፡በሐሰት፡ቃል፡ታምናችኋል።
፱፤ ትሰርቃላችሁ÷ትገድላላችሁ÷ታመነዝራላችሁ÷በሐሰትም፡ትምላላችሁ÷ለበኣልም፡ታጥናላችሁ÷የማታውቋቸውንም፡እንግዶች፡አማልክት፡ትከተላላችሁ፤
፲፤ መጣችሁም÷ስሜም፡በተጠራበት፡በዚህ፡ቤት፡በፊቴ፡ቆማችሁ፡— ይህን፡አስጸያፊ፡የሆነ፡ነገርን፡ሁሉ፡አላደረግንም፡አላችሁ።
፲፩፤ ይህስ፡ስሜ፡የተጠራበት፡ቤት፡በዓይናችሁ፡የሌቦች፡ዋሻ፡ሆኖአልን? እነሆ÷እኔ፡አይቻለሁ÷ይላል፡እግዚአብሔር።
፲፪፤ ነገር፡ግን፡በቀድሞ፡ዘመን፡ስሜን፡ወዳሳደርሁበት፡በሴሎ፡ወደ፡ነበረው፡ስፍራዬ፡ሂዱ÷ከሕዝቤም፡ከእስራኤል፡ክፋት፡የተነሣ፡ያደረግሁበትን፡እዩ።
፲፫፤ አሁንም፡ይህን፡ነገር፡ሁሉ፡ስላደረጋችሁ÷በማለዳም፡ተነሥቼ፡በተናገርኋችሁ፡ጊዜ፡ስላልሰማችሁ÷በጠራኋችሁም፡ጊዜ፡ስላልመለሳችሁ÷
፲፬፤ ስለዚህ፡በሴሎ፡እንዳደረግሁ፡እንዲሁ፡ስሜ፡በተጠራበት፡በምትታመኑበት፡ቤት፡ለእናንተና፡ለአባቶቻችሁም፡በሰጠኋችሁ፡ስፍራ፡አደርጋለሁ።
፲፭፤ የኤፍሬምንም፡ዘር፡ሁሉ÷ወንድሞቻችሁን፡ሁሉ፡እንደ፡ጣልሁ÷እንዲሁ፡ከፊቴ፡እጥላችኋለሁ።
፲፮፤ እንግዲህም፡አልሰማህምና፡ስለዚህ፡ሕዝብ፡አትጸልይ፡ስለ፡እነርሱም፡ልመናና፡ጸሎት፡አታድርግ፤አትማልድላቸው።
፲፯፤ እነርሱስ፡በይሁዳ፡ከተሞች፡ውስጥና፡በኢየሩሳሌም፡አደባባይ፡ላይ፡የሚያደርጉትን፡አታይምን?
፲፰፤ ያስቈጡኝ፡ዘንድ÷ለሰማይ፡ንግሥት፡እንጎቻ፡እንዲያደርጉ፡ለሌሎችም፡አማልክት፡የመጠጥ፡ቍርባን፡እንዲያፈስሱ፡ልጆች፡እንጨት፡ይሰበስባሉ÷አባቶችም፡እሳት፡ያነድዳሉ÷ሴቶችም፡ዱቄት፡ይለውሳሉ።
፲፱፤ እኔን፡ያስቈጣሉን? ይላል፡እግዚአብሔር፤ለፊታቸ

፳፡ ውስ፡እፍረት፡አይደለምን? እንግዲህም፡ ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— እነሆ፥ ቍጣዬና፡መዓቴ፡በዚህ፡ስፍራ፡ላይ፥በሰ ውና፡በእንስሳ፡ላይ፥በዱር፡ዛፎችና፡በም ድር፡ፍሬ፡ላይ፡ይፈስሳል፤ይነድዳል፥አይ ጠፋምም።

፳፩፡ እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— ለሌላ፡ መሥዋዕታችሁ፡የሚቃጠለውን፡መሥዋዕታ ፳፪፡ ችሁን፡ጨምሩ፥ሥጋውንም፡ብሉ። ከግብጽ፡ ምድር፡በወጣኋችሁ፡ቀን፡ስለሚቃጠል፡መሥ ዋዕትና፡ስለ፡ሌላ፡መሥዋዕት፡ለአባቶቻ ችሁ፡አልተናገርሁምና፥አላዘዝኋቸውምም። ፳፫፡ ነገር፡ግን፡— ቃሌን፡ስሙ፥እኔም፡አምላክ፡ እሆናችኋለሁ፡እናንተም፡ሕዝብ፡ትሆኑኛላ ችሁ፤መልካምም፡ይሆንላችሁ፡ዘንድ፡በዘዝኋ ችሁ፡መንገድ፡ሁሉ፡ሂዱ፡ብዬ፡በዚህ፡ነገር፡ ፳፬፡ አዘዝኋቸው። ነገር፡ግን፡በክፉ፡ልባቸው፡ አሳብና፡እልከኝነት፡ሄዱ፡ወደ፡ፊትም፡ሳይ ሆን፡ወደ፡ኋላቸው፡ሄዱ፡እንጂ፡አልሰሙም፡ ፳፭፡ ጆሮአቸውንም፡አላዘነበሉም። አባቶቻችሁ፡ ከግብጽ፡ምድር፡ከወጡበት፡ቀን፡ጀምሮ፡ እስከ፡ዛሬ፡ድረስ፥በየዕለቱ፡እየማለድሁ፡ ባሪያዎቼን፡ነቢያትን፡ሁሉ፡ልኬባችሁ፡ነበር። ፳፮፡ ነገር፡ግን፡አንገታቸውን፡አደነደኑ፡እንጂ፡ አልሰሙኝም፡ጆሮአቸውንም፡አላዘነበሉም፤ አባቶቻቸውም፡ከደረጉት፡ይልቅ፡የባሰ፡ አደረጉ።

፳፯፡ በዚህም፡ቃል፡ሁሉ፡ትነግራቸዋለህ፥ ነገር፡ግን፡አይሰሙህም፤ትጠራቸውማለህ፥ ፳፰፡ ነገር፡ግን፡አይመልሱልህም። አንተም፡— የአምላኩን፡የእግዚአብሔርን፡ቃል፡ያል ሰማ፥ተግሣጽንም፡ያልተቀበለ፡ሕዝብ፡ ይህ፡ነው፤እውነት፡ጠፍቶአል፡ከአፋቸውም፡ ተቈርጦአል፡ትላቸዋለህ።

፳፱፡ እግዚአብሔር፡የቍጣውን፡ትውልድ፡ጥሎ አልና፥ትቶታልምና፡ጠጕርሽን፡ቍረጪ፥ ጣዪውም፥በወናዎች፡ከረብቶችም፡ላይ፡ ፴፡ አሙሽ። የይሁዳ፡ልጆች፡በፊቴ፡ክፉን፡ ነገር፡ሠርተዋል፥ይላል፡እግዚአብሔር፤ያረ ከሱትም፡ዘንድ፡ስሜ፡በተጠራበት፡ቤት፡ ፴፩፡ ርኵሰታቸውን፡አኑረዋል። እኔም፡ያላዘዝሁ ትንና፡በልቤ፡ያላሰብሁትን፥ወንዶችና፡ ሴቶች፡ልጆቻቸውን፡በእሳት፡ያቃጥሉ፡ ዘንድ፡በሄኖም፡ልጅ፡ሸለቆ፡ያለችውን፡ ፴፪፡ የቶፌትን፡መስገጃዎች፡ሠርተዋል። ስለዚህ፥ እነሆ፥ስፍራ፡ከማጣት፡የተነሣ፡በቶፌት፡ ይቀበራሉና፡የእርድ፡ሸለቆ፡ይባላል፡እንጂ፡ ቶፌት፡ወይም፡የሄኖም፡ልጅ፡ሸለቆ፡ዳግ መኛ፡የማይባልበት፡ዘመን፡ይመጣል፥ይላል፡ ፴፫፡ እግዚአብሔር። የዚህም፡ሕዝብ፡ሬሳ፡ለሰ ማይ፡ወፎችና፡ለምድር፡አራዊት፡መብል፡ ፴፬፡ ይሆናል፥የሚያስፈራራቸውም፡የለም። ምድ ሪቱም፡በድማ፡ትሆናለችና፡ከይሁዳ፡ከተሞ ችና፡ከኢየሩሳሌም፡አደባባይ፡የእልልታን፡ ድምፅና፡የደስታን፡ድምፅ፥የወንድ፡ሙሽ ራን፡ድምፅና፡የሴት፡ሙሽራን፡ድምፅ፡አጠ ፋለሁ።

## ምዕራፍ፡፰።

፩፡ በዚያን፡ዘመን፥ይላል፡እግዚአብሔር፥የይ ሁዳን፡ነገሥታት፡አጥንትና፡የመኳንንቶቹን፡ አጥንት፥የካህናቱን፡አጥንትና፡የነቢያቱን፡ አጥንት፥የኢየሩሳሌምንም፡ሰዎች፡አጥንት፡ ፪፡ ከመቃብራቸው፡ያወጣሉ። በወደዱአቸውና፡ ባመለኩአቸው፥በተከተሉአቸውና፡በፈለጉአ ቸው፥በሰገዱላቸውም፡በፀሐይና፡በጨረቃ፡ በሰማይም፡ሠራዊት፡ሁሉ፡ፊት፡ይዘረጉአ ቸዋል፤አያከማቹአቸውም፡አይቀብሩአቸ ውምም፥በምድርም፡ፊት፡ላይ፡እንደ፡ ፫፡ ጕድፍ፡ይሆናሉ። እኔም፡በሳደድኋቸው፡ ስፍራ፡ሁሉ፡የቀሩ፥ከዚህች፡ክፉ፡ወገን፡ የተረፉ፡ቅሬታዎች፡ሁሉ፥ከሕይወት፡ይልቅ፡ ሞትን፡ይመርጣሉ።

፬፡ እንዲህም፡ትላቸዋለህ፡— እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ይላል፡— የወደቁ፡አይነሡምን? የሳ ፭፡ ተስ፡አይመለስምን? እንግዲህ፡ይህ፡የኢየሩ ሳሌም፡ሕዝብ፡ዘወትር፡ስለ፡ምን፡ወደ፡ ኋላው፡ይመለሳል? ተንኰልን፡ይዞአል፡ሊመ ፮፡ ለስም፡እንቢ፡ብሎአል። አደመጥሁ፡ሰማ ሁም፤ቅንን፡ነገር፡አልተናገሩም፤ማናቸ ውም፡— ምን፡አድርጌአለሁ? ብሎ፡ከክፋቱ፡ ንስሐ፡የገባ፡የለም፤ወደ፡ሰልፍም፡እንደሚ ሮጥ፡ፈረስ፡እያንዳንዱ፡በየመንገዱ፡ይሄዳል። ፯፡ ሽመላ፡በሰማይ፡ጊዜዋን፡አውቃለች፤ዋኖ ስና፡ጨረባ፡ዋልያም፡የመምጣታቸውን፡ ጊዜ፡ይጠብቃሉ፤ሕዝቤ፡ግን፡የእግዚአብ ሔርን፡ፍርድ፡አላወቁም።

፰፡ እናንተስ፡— ጥበበኞች፡ነን፡የእግዚአብሔ ርም፡ሕግ፡ከእኛ፡ጋር፡ነው፡እንዴት፡ትላላ ችሁ? እነሆ፥የጸሐፊ፡ብርዕ፡ሐሰተኛ፡ነው፡ ፱፡ በሐሰትም፡አድርጎአል። ጥበበኞች፡አፍረ ዋል፡ደንግጠውማል፡ተማርከውማል፤እነሆ፥ የእግዚአብሔርን፡ቃል፡ጥለዋል፤ምን፡ዓይ ፲፡ ነት፡ጥበብ፡አላቸው? ከታናሹ፡ጀምሮ፡እስከ፡ ታላቁ፡ድረስ፡ሁሉ፡ስስትን፡ያስባሉና፥ከነ ቢዩም፡ጀምሮ፡እስከ፡ካህኑ፡ድረስ፡ሁሉ፡ በተንኰል፡ያደርጋሉና፡ስለዚህ፡ሚስቶቻቸ ውን፡ለሌሎች፥እርሻቸውንም፡ለሚወርሱብ ፲፩፡ ቸው፡እሰጣለሁ። የሕዝቤንም፡ሴት፡ልጅ፡ ስብራት፡በጥቂቱ፡ይፈውሳሉ፤ሰላም፡ሳይ ፲፪፡ ሆን፡— ሰላም፡ሰላም፡ይላሉ። አስጸያፊ፡ ነገርን፡ስለ፡ሠሩ፡አፍረዋልን? ምንም፡አላ ፈሩም፥እፍረትንም፡አላወቁም፤ስለዚህ፡ ከሚወድቁ፡ጋር፡ይወድቃሉ፤በጕበኘኋቸው፡ ጊዜ፡ይዋረዳሉ፥ይላል፡እግዚአብሔር። ፲፫፡ ፈጽሜ፡አጠፋችኋለሁ፥ይላል፡እግዚአብ ሔር፤በወይን፡ላይ፡ፍሬ፥በበለስ፡ዛፍ፡ላይ፡ በለስ፡አይሆንም፥ቅጠልም፡ይረግፋል፤

የሚያልፉባቸውንም፡ሰጠኋቸው።

፲፬ ዝም፡ብለን፡ለምን፡እንቀመጣለን? እግዚአብሔርን፡ስለ፡በደልን፡አምላካችን፡እግዚአብሔር፡አጥፍቶናልና÷የሐሞትንም፡ውኃ፡አጠጥቶናልና፡ተሰብሰባችሁ፡ወደ፡ተመሸጉ፡ከተሞች፡እንግባ፡በዚያም፡እንጥፋ።
፲፭ ሰላምን፡በተስፋ፡ተጠባበቅን÷መልካምም፡አልተገኘም፤መጠገንን፡በተስፋ፡ተጠባበ
፲፮ ቅን÷እነሆም÷ድንጋጤ፡ሆነ። የፈረሶቹ፡ድምፅ፡ከዳን፡ተሰማ፤ከአርበኞች፡ፈረሶች፡ማሽካካት፡የተነሣ፡ምድር፡ሁሉ፡ተንቀጠቀጠች፤መጡም፡ምድሪቱንና፡በእርስዋም፡ያለውን፡ሁሉ÷ከተማይቱንና፡የተቀመጡብት
፲፯ ንም፡በሉ። እነሆ÷እስማት፡የማይከለከላቸውን፡እባቦችንና፡እፉኝቶችን፡እሰድድባችኋለሁ፤እነርሱም፡ይነድፉአችኋል።
፲፰ ኀዘኔ፡የማይጽናና፡ነው÷ልቤም፡በው
፲፱ ስጤ፡ደክሞአል። እነሆ፦ እግዚአብሔር፡በጽዮን፡የለምን? ወይስ፡ንጉሥዋ፡በእርስዋ፡ዘንድ፡የለምን? የሚል፡የወገኔ፡ሴት፡ልጅ፡ጩኸት፡ድምፅ፡ከሩቅ፡አገር፡ተሰማ። በተቀረጹ፡ምስሎቻቸውና፡በባዕድ፡ከንቱነትስ፡
፳ ያስቈጡኝ፡ስለ፡ምንድር፡ነው? መከሩ፡አልፎአል÷በጋው፡ሄዶአል÷እኛም፡አልዳን
፳፩ ንም። በሕዝቤ፡ሴት፡ልጅ፡ስብራት፡እኔ፡ተሰብሬአለሁ፡ጠቍሬማለሁ፤አድናቆትም፡
፳፪ ይዞኛል። በገለዓድ፡የሚቀባ፡መድኃኒት፡የለምን? ወይስ፡በዚያ፡ሐኪም፡የለምን? የወገኔ፡ሴት፡ልጅ፡ፈውስ፡ስለ፡ምን፡አልሆነም?

## ምዕራፍ፡፱።

፩ ተወግተው፡ስለ፡ሞቱ፡ስለ፡ሕዝቤ፡ሴት፡ልጅ፡ሰዎች፡ሌሊትና፡ቀን፡አለቅስ፡ዘንድ፡ራሴ፡ውኃ÷ዓይኔም፡የእንባ፡ምንጭ፡በሆነ
፪ ልኝ! ሁሉም፡አመንዝሮች÷የአታላዮች፡ጉባኤ፡ናቸውና፡ሕዝቤን፡እተዋቸው፡ዘንድ፡ከእነርሱም፡እለይ፡ዘንድ፡በምድረ፡በዳ፡የመንገደኞች፡ማደሪያን፡ማን፡በሰጠኝ?
፫ ምላሳቸውን፡ስለ፡ሐሰት፡እንደ፡ቀስት፡ገተሩ፤በምድር፡በረቱ፡ነገር፡ግን፡ለእውነት፡አይደለም፤ከክፋት፡ወደ፡ክፋት፡ይሄዳሉና፡እኔንም፡አላወቁምና÷ይላል፡እግዚ
፬ አብሔር። ወንድምም፡ሁሉ፡ያሰናክላልና÷ባልንጀራም፡ሁሉ፡ያማልና፡እናንተ፡ሁሉ፡ከባልንጀሮቻችሁ፡ተጠንቀቁ÷በወንድሞቻ
፭ ችሁም፡አትታመኑ። ሰውም፡ሁሉ፡ባልንጀራውን፡ያታልላል፡በእውነትም፡አይናገርም፤ሐሰትን፡መናገርንም፡ምላሳቸው፡ተምሮአል÷ክፉንም፡ለማድረግ፡ይደክማሉ።
፮ ማደሪያህ፡በሽንገላ፡መካከል፡ነው÷ከሽንገላም፡የተነሣ፡እኔን፡ያውቁኝ፡ዘንድ፡እንቢ፡ብለዋል÷ይላል፡እግዚአብሔር።
፯ ስለዚህ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፦ እነሆ÷አቀልጣቸዋለሁ፡እፈትናቸውማለሁ፤ስለ፡ሕዝቤ፡ሴት፡ልጅ፡ከፋት፡ከዚህ፡ሌላ፡የማደርገው፡ምንድር፡ነው?
፰ ምላሳቸው፡የተሳለ፡ፍላጻ፡ነው፤ሽንገላን፡ይናገራሉ፤ሰው፡ከባልንጀራው፡ጋር፡በሰላም፡ይናገራል÷በልቡ፡ግን፡ያደባበታል።
፱ በውኑ፡ስለዚህ፡ነገር፡አልቀሥፍምን? ይላል፡እግዚአብሔር፤ነፍሴስ፡እንደዚህ፡ባለ፡ሕዝብ፡ላይ፡አትበቀልምን?
፲ ለተራሮች፡ልቅሶን፡ለምድረ፡በዳ፡ማሰማርያዎችም፡ዋይታን፡አነሣለሁ÷ሰው፡እንዳያልፍባቸው፡በእሳት፡ተቃጥለዋልና። ሰዎችም፡የከብቱን፡ድምፅ፡አይሰሙም፤ከሰማይ፡ወፎች፡ጀምሮ፡እስከ፡እንስሳ፡ድረስ፡ሸሽ
፲፩ ተው፡ሄደዋል። ኢየሩሳሌምንም፡የፍርስራሽ፡ክምር፡የቀበሮም፡ማደሪያ፡አደርጋታለሁ÷የይሁዳንም፡ከተሞች፡ሰው፡የማይቀመጥባት፡ባድማ፡አደርጋቸዋለሁ።
፲፪ ይህን፡የሚያስተውል፡ጠቢብ፡ሰው፡ማን፡ነው? ያወራስ፡ዘንድ፡የእግዚአብሔር፡አፍ፡ለማን፡ተናገረ? ሰው፡እንዳያልፍባት፡ምድርስ፡ስለ፡ምን፡ጠፋች÷እንደ፡ምድረ፡በዳስ፡
፲፫ ስለ፡ምን፡ተቃጠለች? እግዚአብሔርም፡እንዲህ፡አለ፦ የሰጠኋቸውን፡ሕጌን፡ትተ
፲፬ ዋልና÷ቃሌንም፡አልሰሙምና÷ነገር፡ግን፡የልባቸውን፡ምኞትና፡አባቶቻቸው፡ያስተ
፲፭ ማሩአቸውን፡በኣሊምን፡ተከትለዋልና፡ስለዚህ፡የእስራኤል፡አምላክ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፦ እነሆ÷ይህን፡ሕዝብ፡እሬትን፡አበላዋለሁ፡የሐሞትንም፡ውኃ፡አጠ
፲፮ ጣዋለሁ። እነርሱና፡አባቶቻቸውም፡ባላወቁአቸው፡አሕዛብ፡መካከል፡እበትናቸዋለሁ÷እስካጠፋቸውም፡ድረስ፡በስተ፡ኋላቸው፡ሰይፍን፡እሰድድባቸዋለሁ።
፲፯ እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፦ እንዲመጡ፡አልቃሾች፡ሴቶችን፡ጥሩ፤እንዲመ
፲፰ ጡም፡ወደ፡ብልሃተኞች፡ሴቶች፡ላኩ፤ዓይኖቻችንም፡እንባ፡እንዲያፈስሱ፡የዓይናችንም፡ሽፋሽፍቶች፡ውኃን፡እንዲያፈልቁ፡
፲፱ ፈጥነው፡ለእኛ፡ልቅሶውን፡ይያዙ። በጽዮን፦ እንዴት፡ተበዘበዝን! ምድርንም፡ትተናልና÷ቤቶቻችንንም፡አፍርሰዋልና፡እንዴት፡አፈርን! የሚል፡የልቅሶ፡ድምፅ፡ተሰም
፳ ቶአል። እናንተ፡ሴቶች፡ሆይ÷የእግዚአብሔርን፡ቃል፡ስሙ÷ጆሮአችሁም፡የአፉን፡ቃል፡ትቀበል÷ለሴቶች፡ልጆቻችሁም፡ልቅሶውን÷እያንዳንዳችሁም፡ለባልንጀሮቻችሁ፡
፳፩ ዋይታውን፡አስተምሩ። ሕፃናቱን፡ከመንገድ፡ጕልማሶቹንም፡ከአደባባይ፡ያጠፋ፡ዘንድ፡ሞት፡ወደ፡መስኮታችን፡ደርሶአል፡ወደ፡
፳፪ አዳራሻችንም፡ውስጥ፡ገብቶአል። የሰውም፡ሬሳ፡እንደ፡ጕድፍ፡በእርሻ፡ላይ÷ማንምም፡እንደማይሰበስበው፡ከአጫጆች፡በኋላ፡እንደሚቀር፡ቃርሚያ፡ይወድቃል።

፳፫ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ጠቢብ ፡ በጥበቡ ፡ አይመካ ፥ ኃያልም ፡ በኃይሉ ፡ አይ መካ ፥ ባለ ፡ ጠጋም ፡ በብልጥግናው ፡ አይመካ ፤ ፳፬ ነገር ፡ ግን ፡ የሚመካው ፡— ምሕረትንና ፡ ፍር ድን ፡ ጽድቅንም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የማደርግ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ መሆኔን ፡ በማወቁና ፡ በማስተ ዋሉ ፡ በዚህ ፡ ይመካ ፤ ደስ ፡ የሚያሰኙኝ ፡ እነ ዚህ ፡ ናቸውና ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፳፭፡፳፮ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ያልተገረዙ ፡ ናቸውና ፥ የእ ስራኤልም ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ልባቸው ፡ ያልተገረዘ ፡ ነውና ፡ የተገረዙትን ፡ ሁሉ ፥ ግብጽንና ፡ ይሁ ዳን ፡ ኤዶምያስንም ፡ የአሞንንም ፡ ልጆች ፡ ሞዓ ብንም ፡ በምድረ ፡ በዳም ፡ የተቀመጡትን ፡ ጠጕ ራቸውን ፡ በዙሪያ ፡ የተላጩትን ፡ ሁሉ ፥ ባለ መገረዛቸው ፡ እነርሱን ፡ የምቀጣበት ፡ ዘመን ፡ እነሆ ፡ ይመጣል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ እናንተ ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ እግዚአ ብሔር ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ ፪ ስሙ ። እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የአሕዛብን ፡ መንገድ ፡ አትማሩ ፡ ከሰማይ ፡ ምል ፫ ክትም ፡ አትፍሩ ፤ አሕዛብ ፡ ይፈሩታልና ። የአ ሕዛብ ፡ ልማድ ፡ ከንቱ ፡ ነውና ፤ ዛፍ ፡ ከዱር ፡ ይቈረጣል ፥ በሠራተኛም ፡ እጅ ፡ በመጥረቢያ ፡ ፬ ይሠራል ። በብርና ፡ በወርቅ ፡ ያስጌጡታል ፥ እንዳይናወጥም ፡ በችንካርና ፡ በመዶሻ ፡ ይቸ ፭ ነከሩታል ። እንደ ፡ ተቀረጸ ፡ ዓምድ ፡ ናቸው ፡ እነርሱም ፡ አይናገሩም ፤ መራመድም ፡ አይቻ ላቸውምና ፡ ይሸከሙአቸዋል ። ክፉ ፡ መሥራ ትም ፡ አይቻላቸውምና ፥ ደግሞም ፡ መልካም ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ አይችሉምና ፡ አትፍሩአቸው ።

፮ አቤቱ ፥ እንደ ፡ አንተ ፡ ያለ ፡ የለም ፤ አንተ ፡ ታላቅ ፡ ነህ ፡ ስምህም ፡ በኃይል ፡ ታላቅ ፡ ነው ። ፯ የአሕዛብ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ በአሕዛብ ፡ ጥበበ ኞች ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ በመንግሥታቸውም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ አንተ ፡ ያለ ፡ ስለሌለ ፥ አንተን ፡ መፍራት ፡ ይገባልና ፡ አንተን ፡ የማይፈራ ፡ ፰ ማን ፡ ነው ? በአንድ ፡ ጊዜ ፡ ሰንፈዋል ፥ ደን ቍረውማል ፤ ጣዖታት ፡ የሚያስተምሩት ፡ የእ ፱ ንጨት ፡ ነገር ፡ ብቻ ፡ ነው ። የሠራተኛና ፡ የአ ንጥረኛ ፡ እጅ ፡ ሥራ ፡ የሆነ ፡ ከተርሴስ ፡ ጥፍ ጥፍ ፡ ብር ፡ ከአፌዝም ፡ ወርቅ ፡ ይመጣል ፤ ልብሳቸውም ፡ ሰማያዊና ፡ ቀይ ፡ ግምጃ ፡ ነው ፥ ፲ ሁሉም ፡ የብልሃተኞች ፡ ሥራ ፡ ናቸው ። እግ ዚአብሔር ፡ ግን ፡ እውነተኛ ፡ አምላክ ፡ ነው ፤ እርሱም ፡ ሕያው ፡ አምላክና ፡ የዘላለም ፡ ንጉሥ ፡ ነው ፤ ከቍጣው ፡ የተነሣ ፡ ምድር ፡ ትንቀጠቀ ጣለች ፥ አሕዛብም ፡ መዓቱን ፡ አይችሉም ።

፲፩ እናንተም ፡— ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ ያልፈ ጠሩ ፡ እነዚህ ፡ አማልክት ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ ከሰማይም ፡ በታች ፡ ይጠፋሉ ፡ ትሉአቸዋላ ችሁ ።

፲፪ ምድርን ፡ በኃይሉ ፡ የፈጠረ ፥ ዓለሙን ፡ በጥ በቡ ፡ የመሠረተ ፡ ሰማያትንም ፡ በማስተዋሉ ፡ የዘረጋ ፡ እርሱ ፡ ነው ። ፲፫ ድምፁን ፡ ባሰማ ፡ ጊዜ ፡ ውኆች ፡ በሰማይ ፡ ይሰበሰባሉ ፥ ከምድርም ፡ ዳር ፡ ደመናትን ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ፤ ለዝናብም ፡ መብረቅን ፡ ያደርጋል ፥ ነፋስንም ፡ ከቤተ ፡ መዛ ግብቱ ፡ ያወጣል ። ፲፬ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እውቀት ፡ አጥቶ ፡ ሰንፎአል ፥ አንጥረኛም ፡ ሁሉ ፡ ከቀረ ጸው ፡ ምስል ፡ የተነሣ ፡ አፍሮአል ፤ ቀልጦ ፡ የተሠራ ፡ ምስሉ ፡ ውሸት ፡ ነውና ፥ እስትንፋ ስም ፡ የላቸውምና ። ፲፭ እነርሱ ፡ ምናምንቴና ፡ የቀ ልድ ፡ ሥራ ፡ ናቸው ፤ በተጐበኙ ፡ ጊዜ ፡ ይጠ ፋሉ ። ፲፮ የያዕቆብ ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ እንደ ፡ እነ ዚህ ፡ አይደለም ፤ እርሱ ፡ የሁሉ ፡ ፈጣሪ ፡ ነውና ፤ እስራኤልም ፡ የርስቱ ፡ ነገድ ፡ ነውና ፤ ስሙ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ።

፲፯ በምሽግ ፡ ውስጥ ፡ የተቀመጥሽ ፡ ሆይ ፥ ዕቃ ሽን ፡ ከመሬት ፡ ሰብስቢ ፤ ፲፰ እግዚአብሔር ፡ እን ዲህ ፡ ይላልና ፡— እነሆ ፥ በምድሪቱ ፡ የሚኖሩ ትን ፡ እስኪሰማቸው ፡ ድረስ ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ እወ ነጭፋቸዋለሁ ፥ አስጨንቃቸውማለሁ ።

፲፱ ስለ ፡ ስብራቴ ፡ ወዮልኝ ! ቍስሌም ፡ ክፉ ፡ ነው ፥ እኔ ፡ ግን ፡— በእውነት ፡ የመከራ ፡ ቍስሌ ፡ ነው ፡ እርሱንም ፡ መሸከም ፡ ይገባኛል ፡ አልሁ ። ፳ ድንኳኔ ፡ ተበዘበዘ ፡ አውታሬም ፡ ሁሉ ፡ ተቈ ረጠ ፤ ልጆቼም ፡ ከእኔ ፡ ወጥተው ፡ አይገኙም ፤ ድንኳኔንም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ የሚዘረጋ ፡ መጋረጃዎችንም ፡ የሚያነሣ ፡ የለም ። ፳፩ እረኞች ፡ ሰንፈዋልና ፥ እግዚአብሔርን ፡ አልጠየቁት ምና ፡ አልተከናወነላቸውም ፥ መንጎቻቸውም ፡ ሁሉ ፡ ተበትነዋል ። ፳፪ የወሬን ፡ ድምፅ ፡ ስሙ ፤ እነ ሆም ፥ የይሁዳን ፡ ከተሞች ፡ ባድማና ፡ የቀበሮ ፡ ማደሪያ ፡ ያደርጋቸው ፡ ዘንድ ፡ ከሰሜን ፡ ምድር ፡ ጽኑ ፡ ሽብር ፡ መጥቶአል ።

፳፫ አቤቱ ፥ የሰው ፡ መንገድ ፡ ከራሱ ፡ እንዳይ ደለ ፡ አውቃለሁ ፥ አካሄዱንም ፡ ለማቅናት ፡ ከሚራመድ ፡ ሰው ፡ አይደለም ። ፳፬ አቤቱ ፥ ቅጣኝ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እንዳታዋርደኝ ፡ በመጠን ፡ ይሁን ፡ እንጂ ፡ በቍጣ ፡ አይሁን ። ፳፭ ያዕቆብን ፡ በልተ ውታልና ፥ ውጠውትማልና ፥ አጥፍተውትማ ልና ፥ ማደሪያውንም ፡ አፍርሰዋልና ፡ በማያው ቁህ ፡ አሕዛብ ፡ ስምህንም ፡ በማይጠሩ ፡ ወገ ኖች ፡ ላይ ፡ መዓትህን ፡ አፍስስ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ የመጣው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። ፪ የዚህን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ቃል ፡ ስማ ፥ ለይሁዳም ፡ ሰዎች ፡ በኢ የሩሳሌምም ፡ ለሚኖሩ ፡ ተናገር ፥ ፫፡፬ እንደዚህም ፡ በላቸው ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብ ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ከግብጽ ፡ አገር ፡ ከብ ረት ፡ ምድጃ ፡ በወጣኋቸው ፡ ቀን ፡ ለአባቶቻችሁ ፡ ያዘዝሁትን ፡ የዚህን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ቃል ፡ የማይ ሰማ ፡ ሰው ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፤ አልሁም ፡— ቃሌን ፡ ስሙ ፥ ያዘዝኋችሁንም ፡ ሁሉ ፡ አድርጉ ፤ እን

ዲሁም ፡ እናንተ ፡ ሕዝብ ፡ ትሆኑኛላችሁ ፡ እኔም ፡
፭ አምላክ ፡ እሆናችኋለሁ ። ይህም ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ ወተትና ፡ ማር ፡ የምታፈስሰውን ፡ ምድር ፡
እሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ለአባቶቻችሁ ፡ የማልሁ
ትን ፡ መሐላ ፡ አጸና ፡ ዘንድ ፡ ነው ። እኔም ፡—
አቤቱ ÷ አሜን ፡ ብዬ ፡ መለስሁለት ።

፮ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡— ይህ
ችን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ በይሁዳ ፡ ከተሞችና ፡ በኢ
የሩሳሌም ፡ አደባባይ ፡ ተናገር ÷ እንዲህም ፡
በል ፡— የዚህን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ቃል ፡ ስሙ ፡
፯ አድርጉትም ። አባቶቻችሁን ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡
ካወጣሁበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ÷
በማለዳ ፡ ተነሥቼ ፡ እያስጠነቀቅሁ ፡— ቃሌን ፡
ስሙ ፡ በማለት ፡ አስጠንቅቄአቸው ፡ ነበር ።
፰ እነርሱ ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ በክፉ ፡ ልባቸው ፡ እልከ
ኝነት ፡ ሄዱ ፡ እንጂ ፡ አልሰሙም ፡ ጆሮአቸ
ውንም ፡ አላዘነበሉም ፤ ስለዚህ ፡ ያዘዝኋቸውን ፡
እነርሱም ፡ ያላደረጉትን ፡ የዚህን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
ቃል ፡ ሁሉ ፡ አመጣሁባቸው ።

፱ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡— በይ
ሁዳ ፡ ሰዎችና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በሚኖሩ ፡ ዘንድ ፡
፲ አድማ ፡ ተገኝቶአል ። ቃሌንም ፡ ይሰሙ ፡ ዘንድ ፡
እንቢ ፡ ወዳሉ ፡ ወደ ፡ አባቶቻቸው ፡ ኃጢአት ፡
ተመለሱ ÷ ያመልኩአቸውም ፡ ዘንድ ፡ እንግዶ
ችን ፡ አማልክት ፡ ተከተሉ ፤ የእስራኤል ፡ ቤትና ፡
የይሁዳ ፡ ቤት ፡ ከአባቶቻቸው ፡ ጋር ፡ ያደረግሁ
፲፩ ትን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አፈረሱ ። ስለዚህ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ ሊያመልጡት ፡
የማይችሉትን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አመጣባቸዋለሁ ÷
ወደ ፡ እኔም ፡ ይጮኻሉ ፤ እኔም ፡ አልሰማቸ
፲፪ ውም ። በይሁዳም ፡ ከተሞችና ፡ በኢየሩሳሌም ፡
የሚኖሩ ፡ ሄደው ፡ ወደሚያጥኑላቸው ፡ አማል
ክት ፡ ይጮኻሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በመከራቸው ፡
፲፫ ጊዜ ፡ ከቶ ፡ አያድኑአቸውም ። ይሁዳ ፡ ሆይ ÷
አማልክትህ ፡ እንደ ፡ ከተሞችህ ፡ ቍጥር ፡ እን
ዲሁ ፡ ናቸው ፤ እንደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ መንገ
ዶች ፡ ቍጥር ፡ ለነውረኛ ፡ ነገር ፡ መሠዊያ ÷ እር
ሱም ፡ ለበኣል ፡ ታጥኑበት ፡ ዘንድ ፡ መሠዊያ ÷
፲፬ አድርጋችኋል ። አንተም ፡ ስለዚህ ፡ ሕዝብ ፡
አትጸልይ ፤ ከመከራቸው ፡ የተነሣ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡
በጮኹ ፡ ጊዜ ፡ አልሰማቸውምና ፡ ስለ ፡ እነር
ሱም ፡ ጩኸትና ፡ ልመና ፡ አታድርግ ።

፲፭ ወዳጄ ፡ በቤቴ ፡ ውስጥ ፡ ምን ፡ አላት ? ስእ
ለት ፡ ወይም ፡ የተቀደሰ ፡ ሥጋ ፡ ከፋትሽን ፡
ከአንቺ ፡ ያስወግዳልን ? ወይስ ፡ በእነዚህ ፡ ታመ
፲፮ ልጫለሽን ? እግዚአብሔር ፡ ስምሽን ፡— በመ
ልክም ፡ ፍሬ ፡ የተዋበች ፡ የለመለመች ፡ የወ
ይራ ፡ ዛፍ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ፤ በጽኑ ፡ ፀውሎ ፡
ነፋስ ፡ ጩኸት ፡ እሳትን ፡ አነደደበት ÷ ቅርንጫ
፲፯ ፎችዋም ፡ ተሰብረዋል ። ለበኣልም ፡ በማጠና
ቸው ፡ ያስቈጡኝ ፡ ዘንድ ፡ ለራሳቸው ፡ ስለ ፡
ሠሩአት ፡ ስለ ፡ እስራኤልና ፡ ስለ ፡ ይሁዳ ፡ ቤት ፡
ክፋት ፡ የተከለሽ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ክፉን ፡ ነገር ፡ ተናግሮብሻል ።

፲፰ እግዚአብሔርም ፡ አስታወቀኝ ፡ እኔም ፡ አወ
፲፱ ቅሁ ፤ ሥራቸውንም ፡ ገለጥህልኝ ። እኔም ፡ ለመ
ታረድ ፡ እንደሚነዳ ፡ እንደ ፡ የዋህ ፡ በግ ፡ ጠቦት ፡
ሆንሁ ፤ እነርሱም ፡— ዛፉን ፡ ከፍሬው ፡ ጋር ፡
እንቍረጥ ÷ ስሙም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ እን
ዳይታሰብ ፡ ከሕያዋን ፡ ምድር ፡ እናጥፋው ፡
ብለው ፡ ምክርን ፡ እንዳሰቡብኝ ፡ አላወቅሁም ፡
፳ ነበር ። ኵላሊትንና ፡ ልብን ፡ የምትፈትን ፡ በቅ
ንም ፡ የምትፈርድ ፡ አቤቱ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡
ሆይ ÷ ክርክሬን ፡ ገልጬልሃለሁና ፡ በእነርሱ ፡
፳፩ ላይ ፡ የሚሆን ፡ በቀልህን ፡ ልይ ። ስለዚህም ፡—
በእጃችን ፡ እንዳትሞት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡
ትንቢት ፡ አትናገር ፡ ብለው ፡ ነፍስህን ፡ ስለሚሹ ፡
ስለ ፡ ዓናቶት ፡ ሰዎች ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
፳፪ ይላል ፡— እነሆ ÷ እቀጣቸዋለሁ ፤ ጎበዛዝቶቻ
ቸው ፡ በሰይፍ ፡ ይሞታሉ ÷ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡
፳፫ ልጆቻቸውም ፡ በራብ ፡ ይሞታሉ ፤ በምጐበኛ
ቸውም ፡ ዓመት ፡ በዓናቶት ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡
ነገር ፡ አመጣባቸዋለሁና ፡ ማንም ፡ ከእነርሱ ፡
የሚቀር ፡ የለም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ አቤቱ ÷ ከአንተ ፡ ጋር ፡ በተምዋገትሁ ፡ ጊዜ ፡
አንተ ፡ ጻድቅ ፡ ነህ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡
ስለ ፡ ፍርድ ፡ ልናገር ። የኃጢአተኞች ፡ መን
ገድ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይቃናል ? በደልንስ ፡ ለሚያ
ደርጉ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ደኅንነት ፡ ይሆናል ?
፪ ተክለሃቸዋል ፤ ሥር ፡ ሰድደዋል ፤ አድገዋል ፡
አፍርተውማል ፤ በአፋቸው ፡ አንተ ፡ ቅርብ ፡
፫ ነህ ÷ ከልባቸው ፡ ግን ፡ ሩቅ ፡ ነህ ። አንተ ፡
ግን ÷ አቤቱ ÷ አውቀኸኛል ፤ አይተኸኛል ÷
ልቤንም ፡ በፊትህ ፡ ፈትነሃል ፤ እንደ ፡ በጎች ፡
ለመታረድ ፡ ጐትተህ ፡ ለያቸው ÷ ለመታረድም ፡
፬ ቀን ፡ አዘጋጃቸው ። ምድሪቱ ፡ የምታለቅሰው ÷
የአገሩ ፡ ሣርስ ፡ ሁሉ ፡ የሚደርቀው ፡ እስከ ፡
መቼ ፡ ነው ? የተቀመጡባት ፡ ሰዎች ፡— ፍጻ
ሜያችንን ፡ አያይም ፡ ብለዋልና ፡ ስለ ፡ ክፋታ
ቸው ፡ እንስሶችና ፡ ወፎች ፡ ጠፍተዋል ።

፭ ከእግረኞች ፡ ጋር ፡ በሮጥህ ፡ ጊዜ ፡ እነርሱ ፡
ቢያደክሙህ ÷ ከፈረሶች ፡ ጋር ፡ መታገል ፡ እን
ዴት ፡ ትችላለህ ? በሰላምም ፡ ምድር ፡ ታምነህ ፡
ብትቀመጥ ÷ በዮርዳኖስ ፡ ትዕቢት ፡ እንዴት ፡
፮ ታደርጋለህ ? ወንድሞችህና ፡ የአባትህ ፡ ቤት ፡
እነርሱ ፡ ጭምር ፡ አታልለውሃልና ÷ በኋላህም ፡
ጮኸዋልና ፤ በመልካምም ፡ ቢናገሩህም ፡ አት
ታመናቸው ።

፯ ቤቴን ፡ ትቼአለሁ ፡ ርስቴንም ፡ ጥያለሁ ÷ ነፍ
ሴም ፡ የምትወድዳትን ፡ በጠላቶችዋ ፡ እጅ ፡ አሳ
፰ ልፌ ፡ ሰጥቻለሁ ። ርስቴ ፡ በዱር ፡ እንዳለ ፡
አንበሳ ፡ ሆናብኛለች ፤ ድምፅዋን ፡ አንሥታብ
፱ ኛለች ፤ ስለዚህ ፡ ጠልቻታለሁ ። ርስቴ ፡ እንደ ፡
ዝንጕርጕር ፡ አሞራ ፡ ሆነችብኝን ? አሞሮችስ ፡
በዙሪያዋና ፡ በላይዋ ፡ ሆነዋልን ? ሂዱ ÷ የም
ድር ፡ አራዊትን ፡ ሁሉ ፡ ሰብስቡ ÷ ይበሉም ፡

፲፤ ዘንድ፡ አምጡአቸው ። ብዙ ፡ እረኞች ፡ የወ
ይኑን፡ በታዬን፡ አጥፍተዋል ÷ እድል፡ ፈንታ
ዬንም ፡ ረግጠዋል ፤ የአምሮቴን ፡ እድል ፡
፲፩፤ ፈንታ ፡ ምድረ ፡ በዳ፡ አድርገውታል ። በድማ፡
አድርገውታል ÷ ፈርሶም ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ያለቅ
ሳል ፤ ምድር ፡ ሁሉ ፡ በድማ፡ ሆናለች ፡ በል
፲፪፤ ቡም፡ የሚያስባት ፡ የለም ። በወናዎች ፡ ኮረ
ብቶች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በዝባዦች ፡ መጥተዋል ÷
የእግዚአብሔር፡ ሰይፍ፡ ከምድር፡ዳር፡ጀምሮ፡
እስከ፡ ምድር፡ዳር፡ ድረስ፡ ይበላልና ፤ ለሥጋ፡
፲፫፤ ለባሽ፡ ሁሉ ፡ ሰላም ፡ የለም ። ስንዴን ፡ ዘሩ ፡
እሾህንም ፡ አጨዱ ፤ ደከሙ ÷ ምንም ፡ አልረ
ባቸውም ፤ ስለ፡ እግዚአብሔር ፡ ጽኑ ፡ ቍጣ፡
ከፍሬያችሁ ፡ ታፍራላችሁ ።
፲፬፤ እግዚአብሔር፡ ለሕዝቤ ፡ ለእስራኤል ፡ ያወ
ረስሁትን ፡ ርስት ፡ ለሚነኩት ፡ ክፉዎች ፡ ጐረቤ
ቶች ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— እነሆ ÷ ከም
ድራቸው ፡ እነቅላቸዋለሁ ÷ የይሁዳንም ፡ ቤት ፡
፲፭፤ ከመካከላቸው ፡ እነቅለዋለሁ ። ከነቀልኋቸውም፡
በኋላ ፡ መልሼ ፡ እምራቸዋለሁ ÷ እያንዳንዱ
ንም ፡ ወደ ፡ ርስቱ ፡ እያንዳንዱንም ፡ ወደ ፡
፲፮፤ ምድሩ ፡ እመልሳለሁ ። በበኣል ፡ ይምሉ ፡
ዘንድ ፡ ሕዝቤን ፡ እንዳስተማሩ ፡ በስሜ ፡—
ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! ብለው ፡ ይምሉ ፡
ዘንድ ፡ የሕዝቤን ፡ መንገድ ፡ በትጋት ፡ ቢማሩ ÷
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በሕዝቤ ፡ መካከል ፡ ይመሠረ
፲፯፤ ታሉ ። ባይሰሙኝ ፡ ግን ፡ ያንን ፡ ሕዝብ ፡ ፈጽሜ ፡
እነቅለዋለሁ ፡ አጠፋውማለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚ
አብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይለኛል ፡— ሂድ ÷
ከተልባ ፡ እግር ፡ የተሠራችን ፡ መታጠቂያ ፡
ለአንተ ፡ ግዛ ÷ ወገብህንም ፡ ታጠቅበት ፤ በው
፪፤ ኃውም ፡ ውስጥ ፡ አትንከራት ። እንደ ፡ እግዚ
አብሔርም ፡ ቃል ፡ መታጠቂያን ፡ ገዛሁ ፡ ወገቤ
፫፤ ፬፤ ንም ፡ ታጠቅሁበት ። ሁለተኛም ፡ ጊዜ ፡— የገ
ዛሃትን ፡ በወገብህ ፡ ያለችውን ፡ መታጠቂያ ፡
ወስደህ ፡ ተነሥ ÷ ወደ ፡ ኤፍራጥስም ፡ ሂድ ÷
በዚያም ፡ በተሰነጠቀ ፡ ዓለት ፡ ውስጥ ፡ ሸሽጋት ፡
የሚል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ መጣልኝ ።
፭፤ እግዚአብሔርም ፡ እንዳዘዘኝ ፡ ሄድሁ ፡ በኤፍራ
፮፤ ጥስም ፡ አጠገብ ፡ ሸሸግኋት ። ከብዙ ፡ ቀንም ፡
በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡— ተነሥተህ ፡ ወደ ፡ ኤፍ
ራጥስ ፡ ሂድ ÷ በዚያም ፡ ትሸሽጋት ፡ ዘንድ ፡
ያዘዝሁህን ፡ መታጠቂያ ፡ ከዚያ ፡ ውስጥ ፡ ውሰድ ፡
፯፤ አለኝ ። እኔም ፡ ወደ ፡ ኤፍራጥስ ፡ ሄድሁ ፡ ቆፈ
ርሁም ÷ ከሸሸግሁበትም ፡ ስፍራ ፡ መታጠቂያ
ይቱን ፡ ወሰድሁ ። እነሆም ÷ መታጠቂያይቱ ፡
ተበላሽታ ፡ ነበር ÷ ለምንም ፡ አልረባችም ።
፰፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፱፤ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እንዲሁ ፡ የይሁዳን ፡ ትዕቢት ፡ ታላ
ቁንም ፡ የኢየሩሳሌምን ፡ ትዕቢት ፡ አበላሻለሁ ።

፲፤ ቃሌን ፡ ይሰሙ ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ የሚሉ ÷ በል
ባቸውም ፡ እልከኝነት ፡ የሚሄዱ ÷ ያመልኩአ
ቸውና ፡ ይሰግዱላቸው ፡ ዘንድ ፡ ሌሎችን ፡ አማ
ልክት ፡ የሚከተሉ ፡ እነዚህ ፡ ክፉ ፡ ሕዝብ ፡ አን
ዳች ፡ እንደማትረባ ፡ እንደዚች ፡ መታጠቂያ ፡
፲፩፤ ይሆናሉ ። መታጠቂያ ፡ በሰው ፡ ወገብ ፡ ላይ ፡
እንደምትጣበቅ ÷ እንዲሁ ፡ ሕዝብና ፡ ስም ፡
ምስጋናና ፡ ክብር ፡ ይሆኑልኝ ፡ ዘንድ ፡ የእስራ
ኤልን ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ የይሁዳንም ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡
ከእኔ ፡ ጋር ፡ አጣብቄአለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብ
ሔር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አልሰሙም ።
፲፪፤ ስለዚህ ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ማድጋ ፡ ሁሉ ፡ የወ
ይን ፡ ጠጅ ፡ ይሞላል ፡ ብለህ ፡ ትነግራቸዋለህ ፤
እነርሱም ፡— ማድጋ ፡ ሁሉ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡
እንዲሞላ ፡ በውኑ ፡ እኛ ፡ አናውቅምን ? ይሉ
፲፫፤ ሃል ። አንተም ፡ እንዲህ ፡ ትላቸዋለህ ፡— እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ በዚህች ፡
ምድር ፡ የሚኖሩትን ፡ ሁሉ ÷ በዳዊት ፡ ዙፋን ፡
የሚቀመጡትን ፡ ነገሥታት ፡ ካህናቱንም ፡ ነቢ
ያቱንም ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ የተቀመጡትን ፡
፲፬፤ ሁሉ ፡ በስካር ፡ እሞላቸዋለሁ ። ሰውንም ፡
በሰው ፡ ላይ ÷ አባቶችንና ፡ ልጆችን ፡ በአንድ ፡
ላይ ÷ እቀጠቅጣቸዋለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብ
ሔር ፤ አጠፋቸዋለሁ ፡ እንጂ ፡ አልራራም ÷ አላ
ዝንም ÷ አልምርም ።
፲፭፤ ስሙ ÷ አድምጡ ፤ እግዚአብሔር ፡ ተናግሮ
፲፮፤ አልና ፡ አትታበዩ ። ሳትጨልም ፡ እግራችሁም ፡
በጨለመችው ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ሳትሰናከል ÷
በተስፋ ፡ የምትጠባበቁትን ፡ ብርሃን ፡ ለሞት ፡
ጥላና ፡ ለድቅድቅ ፡ ጨለማ ፡ ሳይለውጠው ፡ ለአ
ምላካችሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ክብርን ፡ ስጡ ።
፲፯፤ ይህን ፡ ባትሰሙ ፡ ነፍሴ ፡ ስለ ፡ ትዕቢታችሁ ፡
በስውር ፡ ታለቅሳለች ፤ የእግዚአብሔርም ፡
መንጋ ፡ ተማርኮአልና ፡ ዓይኔ ፡ ታነባለች ÷ እን
ባንም ፡ ታፈስሳለች ።
፲፰፤ ለንጉሡና ፡ ለንጉሥ ፡ እናት ፡ ለእቴጌይቱ ፡—
የክብራችሁ ፡ አክሊል ፡ ከራሳችሁ ፡ ወርዶአ
፲፱፤ ልና ፡ ተዋርዳችሁ ፡ ተቀመጡ ፡ በል ። የደቡብ ፡
ከተሞች ፡ ተዘግተዋል ÷ የሚከፍታቸውም ፡
የለም ፤ ይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ ተማርኮአል ÷ ፈጽሞ ፡
ተማርኮአል ።
፳፤ ዓይናችሁን ፡ አንሥታችሁ ፡ እነዚህን ፡ ከሰ
ሜን ፡ የሚመጡትን ፡ ተመልከቱ ፤ ለአንቺ ፡ የተ
ሰጠ ፡ መንጋ ÷ የተዋበ ፡ መንጋሽ ÷ ወዴት ፡
፳፩፤ አለ ? ወዳጆችሽ ፡ እንዲሆኑ ፡ ያስተማርሻቸ
ውን ፡ በራስሽ ፡ ላይ ፡ አለቆች ፡ በደረጋቸው ፡
ጊዜ ፡ ምን ፡ ትያለሽ ? እንደ ፡ ወላድ ፡ ሴት ፡ ምጥ ፡
፳፪፤ አይዝሽምን ? በልብሽም ፡— እንዲህ ፡ ያለ ፡
ነገር ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ደረሰብኝ ? ብትዪ ÷ ከኃጢአ
ትሽ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ የልብስሽ ፡ ዘርፍ ፡ ተገል
፳፫፤ ጦአል ፡ ተረከዝሽም ፡ ተገፍፎአል ። በውኑ ፡
ኢትዮጵያዊ ፡ መልኩን ፡ ወይስ ፡ ነብር ፡ ዝንጕ
ርጕርነትን ፡ ይለውጥ ፡ ዘንድ ፡ ይችላልን ? በዚ

ያን ፡ ጊዜ ፡ ክፋትን ፡ የለመዳችሁ ፡ እናንተ ፡
፳፬ ደግሞ ፡ በጎ ፡ ለማድረግ ፡ ትችላላችሁ ። ስለ
ዚህ ፡ እንደሚያልፍ ፡ እብቅ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡
፳፭ ነፋስ ፡ እበትናቸዋለሁ ። ረስተሽኛልና ፥ በሐ
ሰትም ፡ ታምነሻልና ፡ ዕጣሽ ፡ የለካሁልሽም ፡
እድል ፡ ፈንታ ፡ ይህ ፡ ነው ፥ ይላል ፡ እግዚአብ
፳፮ ሔር ። ስለዚህም ፡ የልብስሽን ፡ ዘርፍ ፡ በፊ
ትሽ ፡ እገልጣለሁ ፡ እፍረትሽም ፡ ይታያል ።
፳፯ አስጸያፊ ፡ ሥራሽን ፥ ምንዝርናሽን ፥ ማሽካካ
ትሽን ፥ የግልሙትናሽንም ፡ መዳራት ፡ በኮረብ
ቶች ፡ ላይ ፡ በሜዳም ፡ አይቻለሁ ። ኢየሩሳሌም ፡
ሆይ ፥ ወዮልሽ ! ለመንጻት ፡ እንቢ ፡ ብለሻል ፤
ይህስ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ?

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ ስለ ፡ ድርቅ ፡ የመጣው ፡
፪ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። ይሁዳ ፡
አለቀሰች ፥ ደጆችዋም ፡ በዶ ፡ ሆኑ ፡ በምድ
ርም ፡ ላይ ፡ ጨለሙ ፤ የኢየሩሳሌም ፡ ጩኸት ፡
፫ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎአል ። ታላላቆችም ፡ ብላቴና
ቻቸውን ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ሰደዱ ፤ ወደ ፡ ጕድጓድ ፡
መጡ ፡ ውኃም ፡ አላገኙም ፥ ዕቃቸውንም ፡
ባዶውን ፡ ይዘው ፡ ተመለሱ ፤ አፈሩም ፡ ተዋረ
፬ ዱም ፡ ራሳቸውንም ፡ ተከናነቡ ። በምድር ፡
ላይ ፡ አልዘነበምና ፡ መሬቱ ፡ ስንጥቅጥቅ ፡ ስለ ፡
ሆነ ፡ አራሾች ፡ አፈሩ ፡ ራሳቸውንም ፡ ተከና
፭ ነቡ ። ዋላ ፡ ደግሞ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ወለደች ፥
፮ ሣርም ፡ የለምና ፡ ግልገልዋን ፡ ተወች ። የሜዳ ፡
አህዮችም ፡ በወና ፡ ኮረብታ ፡ ላይ ፡ ቆመዋል ፥
እንደ ፡ ቀበሮም ፡ ወደ ፡ ነፋስ ፡ አለከለኩ ፤ ልም
ላሜም ፡ የለምና ፡ ዓይኖቻቸው ፡ ጠወለጉ ።
፯ አቤቱ ፥ ኃጢአታችን ፡ ብዙ ፡ ነውና ፥ በአ
ንተም ፡ ላይ ፡ ኃጢአት ፡ ሠርተናልና ፡ ኃጢአ
ታችን ፡ ይመሰክርብናል ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡
፰ ስምህ ፡ ብለህ ፡ አድርግ ። አንተ ፡ የእስራኤል ፡
ተስፋ ፡ ሆይ ፡ በመከራም ፡ ጊዜ ፡ የምታድነው ፥
በምድር ፡ እንደ ፡ እንግዳ ፥ ወደ ፡ ማደሪያ ፡
ዘወር ፡ እንደሚል ፡ መንገደኛ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትሆ
፱ ናለህ ? እንዳንቀላፋ ፡ ሰው ፥ ያድንም ፡ ዘንድ ፡
እንደማይችል ፡ ኃያል ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትሆናለህ ?
አንተ ፡ ግን ፥ አቤቱ ፥ በመካከላችን ፡ ነህ ፡
እኛም ፡ በስምህ ፡ ተጠርተናል ፤ አትተወን ።
፲ እግዚአብሔር ፡ ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፦ መቅበዝበዝን ፡ ወድደዋል ፡ እግራ
ቸውንም ፡ አልከለከሉም ፤ ስለዚህ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በእነርሱ ፡ ደስ ፡ አይለውም ፥ በደላቸው
ንም ፡ አሁን ፡ ያስባል ፡ ኃጢአታቸውንም ፡
፲፩ ይቀጣል ። እግዚአብሔርም ፦ ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡
፲፪ ስለ ፡ መልካም ፡ አትጸልይላቸው ። በጾሙ ፡
ጊዜ ፡ ጸሎታቸውን ፡ አልሰማም ፤ የሚቃጠለ
ውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የእህሉን ፡ ቍርባን ፡ ባቀ
ረቡ ፡ ጊዜ ፡ አልቀበላቸውም ፤ በሰይፍና ፡ በራብ ፡
በቸነፈርም ፡ አጠፋቸዋለሁ ፡ አለኝ ።
፲፫ እኔም ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ ወዮ !
እነሆ ፥ ነቢያት ፦ በእውነት ፡ ሰላምን ፡ በዚህ ፡
ስፍራ ፡ እሰጣችኋለሁ ፡ እንጂ ፡ ሰይፍን ፡ አታ
ዩም ፥ ራብም ፡ አያገኛችሁም ፡ ይሉአቸዋል ፡
፲፬ አልሁ ። እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፦
ነቢያቱ ፡ ውሸት ፡ በስሜ ፡ ትንቢት ፡ ይናገራሉ ፤
አላክኋቸውም ፥ አላዘዝኋቸውም ፥ አልተናገ
ርኋቸውም ፤ የውሸቱን ፡ ራእይ ፡ ምዋርትንም ፡
ከንቱንም ፡ ነገር ፡ የልባቸውንም ፡ ሽንገላ ፡ ይሰ
፲፭ ብኩላችኋል ። ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በስሜ ፡
ትንቢት ፡ ስለሚናገሩ ፡ ነቢያት ፦ በዚህች ፡
አገር ፡ ሰይፍና ፡ ራብ ፡ አይሆንም ፡ ስለሚሉ ፡
ስላላክኋቸው ፡ ነቢያት ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እነ
፲፮ ዚያ ፡ በሰይፍና ፡ በራብ ፡ ይጠፋሉ ። ትንቢት ፡
የሚናገሩላቸውም ፡ ሰዎች ፡ ከራብና ፡ ከሰይፍ ፡
የተነሣ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አደባባይ ፡ ይበተናሉ ፤
ክፋታቸውንም ፡ አፈስስባቸዋለሁና ፡ እነርሱ
ንና ፡ ሚስቶቻቸውን ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆ
፲፯ ቻቸውንም ፡ የሚቀብራቸው ፡ አይገኝም ። እን
ደዚህም ፡ ብለህ ፡ ትነግራቸዋለህ ፦ የወገኔ ፡
ልጅ ፡ ድንግሊቱ ፡ በታላቅ ፡ ስብራትና ፡ እጅግ ፡
ክፉ ፡ በሆነ ፡ ቍስል ፡ ተሰብራለችና ፡ ዓይኖቼ ፡
ሌሊትና ፡ ቀን ፡ ሳያቋርጡ ፡ እንባ ፡ ያፍስሱ ።
፲፰ ወደ ፡ ሜዳ ፡ ብወጣ ፥ እነሆ ፥ በሰይፍ ፡ የሞቱ ፡
አሉ ፤ ወደ ፡ ከተማም ፡ ብገባ ፥ እነሆ ፥ በራብ ፡
የከሱ ፡ አሉ ፤ ነቢዩና ፡ ካህኑም ፡ ወደማያው
ቋት ፡ አገር ፡ ሄደዋልና ።
፲፱ በውኑ ፡ ይሁዳን ፡ ፈጽመህ ፡ ጥለኸዋልን ? ነፍ
ስህስ ፡ ጽዮንን ፡ ጠልታታለችን ? ስለ ፡ ምን ፡
መታኸን ? ፈውስስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ የለንም ? ሰላ
ምን ፡ በተስፋ ፡ ተጠባበቅን ፥ መልካምም ፡ አል
ተገኘም ፤ ፈውስን ፡ በተስፋ ፡ ተጠባበቅን ፥ እነ
፳ ሆም ፥ ድንጋጤ ፡ ሆነ ። አቤቱ ፥ በአንተ ፡ ላይ ፡
ኃጢአትን ፡ ሠርተናልና ፡ ክፋታችንንና ፡ የአ
፳፩ ባቶቻችንን ፡ በደል ፡ እናውቃለን ። ስለ ፡ ስምህ ፡
ብለህ ፡ አትናቀን ፥ የክብርህንም ፡ ዙፋን ፡ አታ
ስነውር ፤ ከእኛ ፡ ጋርም ፡ ያደረግኸውን ፡
ቃል ፡ ኪዳንህን ፡ አስብ ፡ እንጂ ፡ አታፍርስ ።
፳፪ በውኑ ፡ በአሕዛብ ፡ ጣዖታት ፡ መካከል ፡ ያዘ
ንብ ፡ ዘንድ ፡ የሚችል ፡ ይገኛልን ? ወይስ ፡
ሰማይ ፡ ዝናብ ፡ ማፍሰስ ፡ ይችላልን ? አቤቱ ፡
አምላካችን ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ አይደለህምን ?
አንተ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አድርገሃልና ፡ ስለ
ዚህ ፡ አንተን ፡ በተስፋ ፡ እንጠባበቃለን ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ እንደዚህ ፡ አለኝ ፦
ሙሴና ፡ ሳሙኤል ፡ በፊቴ ፡ ቢቆሙም ፥ ልቤ ፡
ወደዚህ ፡ ሕዝብ ፡ አይዘነብልም ፤ ከፊቴ ፡ ጣላ
፪ ቸው ፤ ይውጡ ። እነርሱም ፦ ወዴት ፡ እን
ውጣ ፡ ቢሉህ ፥ አንተ ፦ እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፦ ለሞት ፡ የሆነ ፡ ወደ ፡ ሞት ፥
ለሰይፍም ፡ የሆነ ፡ ወደ ፡ ሰይፍ ፥ ለራብም ፡
የሆነ ፡ ወደ ፡ ራብ ፥ ለምርኮም ፡ የሆነ ፡ ወደ ፡
፫ ምርኮ ፡ ትላቸዋለህ ። ሰይፍን ፡ ለመግደል ፡ ውሾ

ችንም ፡ ለመጐተት ፡ የሰማያትንም ፡ ወፎች ፡
የምድርንም ፡ አራዊት ፡ ለመብላትና ፡ ለማጥፋት ÷
አራቱን ፡ ዓይነት ፡ ጥፋት ፡ አዝዝባቸዋለሁ ÷
፬ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡
የሕዝቅያስ ፡ ልጅ ፡ ምናሴ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ስላ
ደረገው ፡ ሁሉ ፡ በምድር ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡
መካከል ፡ ለመከራ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣቸዋለሁ ።
፭ ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ÷ የሚራራልሽ ፡ ማን ፡
ነው ? የሚያዝንልሽስ ፡ ማን ፡ ነው ? ወይስ ፡
ስለ ፡ ደኅንነትሽ ፡ ይጠይቅ ፡ ዘንድ ፡ ፈቀቅ ፡
፮ የሚል ፡ ማን ፡ ነው ? አንቺ ፡ እኔን ፡ ጥለሽል ÷
ይላል ፡ እግዚአብሔር ÷ ወደ ፡ ኋላሽም ፡ ተመ
ልሰሻል ፤ ስለዚህ ፡ እጄን ፡ በአንቺ ፡ ላይ ፡ ዘር
ግቼ ፡ አጥፍቼሻለሁ ፤ ከይቅርታ ፡ ደክሜአለሁ ።
፯ በአገርም ፡ ደጆች ፡ ውስጥ ፡ በመንሽ ፡ አበጥሬ
አቸዋለሁ ፤ የወላድ ፡ መካን ፡ አድርጌአቸዋለሁ ÷
ሕዝቤንም ፡ አጥፍቼአለሁ ፤ ከመንገዳቸውም ፡
፰ አልተመለሱም ። መበለቶቻቸውም ፡ ከበሕር ፡
አሸዋ ፡ ይልቅ ፡ በዝተውብኛል ፤ በብላቴኖች ፡
እናት ፡ ላይ ፡ በቀትር ፡ ጊዜ ፡ አጥፊውን ፡ አም
ጥቻለሁ ፤ ጣርንና ፡ ድንጋጤን ፡ በድንገት ፡ አም
፱ ጥቼባታለሁ ። ሰባት ፡ የወለደች ፡ ደከማለች ÷
ነፍስዋንም ፡ አውጥታለች ፤ ቀን ፡ ገና ፡ ሳለ ፡
ፀሐይዋ ፡ ገብታባታለች ፤ አፍራለች ፡ ተዋርዳማ
ለች ፤ የተረፉትንም ፡ በጠላቶቻቸው ፡ ፊት ፡
ለሰይፍ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣለሁ ።
፲ እናቴ ፡ ሆይ ÷ ወዮልኝ ፤ ለምድር ፡ ሁሉ ፡ የክ
ርክርና ፡ የጥል ፡ ሰው ፡ የሆንሁትን ፡ ወለድሽኝ ፤
ለማንም ፡ አላበደርሁም ÷ ማንም ፡ ለእኔ ፡ አላበደ
፲፩ ረም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ሁሉ ፡ ይረግመኛል ። እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— በእውነት ፡ ለደ
ኅንነትህ ፡ አጸናሃለሁ ፤ በእውነት ፡ በመከራና ፡
በጭንቅ ፡ ጊዜ ፡ ጠላትህ ፡ እንዲለምንህ ፡ አደር
፲፪ ገዋለሁ ። በውኑ ፡ ብረትን ÷ የሰሜንን ፡ ብረት ÷
ናስንም ፡ የሚሰብር ፡ አለን ?
፲፫ በዳርቻህ ፡ ሁሉ ፡ ስላለ ፡ ኃጢአትህ ፡ ሁሉ ፡
ባለጠግነትህንና ፡ መዝገብህን ፡ ለመበዝበዝ ፡
፲፬ በከንቱ ፡ እሰጣለሁ ። የምታቃጥላችሁ ፡ እሳት ፡
ከቍጣዬ ፡ ትነድዳለችና ፡ ከጠላቶችህ ፡ ጋር ፡
ወደማታውቀው ፡ ምድር ፡ አሳልፍሃለሁ ።
፲፭ አቤቱ ÷ አንተ ፡ ታውቃለህ ፤ አስበኝ ፡ ጐብ
ኘኝም ፡ የሚያሳድዱኝንም ፡ ተበቀላቸው ፡
እንጂ ፡ አትታገሣቸው ፤ ስለ ፡ አንተ ፡ ስድብን ፡
፲፮ እንደ ፡ ታገሥሁ ፡ እወቅ ። ቃልህ ፡ ተገኝቶአል ፡
እኔም ፡ በልቼዋለሁ ፤ አቤቱ ÷ የሠራዊት ፡ አም
ላክ ፡ ሆይ ÷ በስምህ ፡ ተጠርቻለሁና ፡ ቃልህ ፡
፲፯ ሐሤትና ፡ የልብ ፡ ደስታ ፡ ሆነኝ ። በዋዘኞችና ፡
በደስተኞች ፡ ጉባኤ ፡ አልተቀመጥሁም ፤ ቍጣን ፡
ሞልተህብኛልና ፡ በእጅህ ፡ ፊት ፡ ለብቻዬ ፡
፲፰ ተቀመጥሁ ። ስለ ፡ ምን ፡ ሕመሜ ፡ አዘወተረኝ ?
ቍስሌስ ፡ ስለምን ፡ የማይፈወስ ፡ ሆነ ? ስለ ፡
ምንስ ፡— አልሽርም ፡ አለ ? በውኑ ፡ እንደ ፡ ሐሰ
ተኛ ፡ ምንጭ ÷ እንዳልታመነች ፡ ውኃ ፡ ትሆነ
ኛለህን ?

፲፱ ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ብትመለስ ፡ እመልስሃለሁ ፡ በፊቴም ፡ ትቆማለህ ፤
የከበረውንም ፡ ከተዋረደው ፡ ብትለይ ፡ እንደ ፡
አፌ ፡ ትሆናለህ ፤ እነርሱ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ይመለ
ሳሉ ÷ አንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ አትመለስም ።
፳ ለዚህም ፡ ሕዝብ ፡ የተመሸገ ፡ የናስ ፡ ቅጥር ፡
አደርግሃለሁ ፤ ይዋጉሃል ፡ እኔ ፡ ግን ፡ ለማዳን ፡
፳፩ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነኝና ፡ አያሸንፉህም ። ከክፉ ፡
ሰዎችም ፡ እጅ ፡ እታደግሃለሁ ÷ ከጨካኞችም ፡
ጡጫ ፡ እቤዥሃለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡
፪ ሲል ፡ መጣ ፡— በዚህ ፡ ስፍራ ፡ ሚስት ፡ አታ
ግባ ÷ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆችም ፡ አይሁኑ
፫ ልህ ። እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡ ስፍራ ፡ ስለ ፡
ተወለዱ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ÷ ስለ ፡
ወለዱአቸውም ፡ ስለ ፡ እናቶቻቸው ÷ በዚህ
ችም ፡ ምድር ፡ ስለ ፡ ወለዱአቸው ፡ ስለ ፡ አባቶቻ
፬ ቸው ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— በክፉ ፡ ሞት ፡ ይሞ
ታሉ ፤ አይለቀስላቸውም ፡ አይቀበሩምም ÷
በመሬትም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ጕድፍ ፡ ይሆናሉ ፤ በሰ
ይፍና ፡ በራብ ፡ ይጠፋሉ ÷ ሬሳቸውም ፡ ለሰ
ማይ ፡ ወፎችና ፡ ለምድር ፡ አራዊት ፡ መብል ፡
ይሆናሉ ።
፭ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ሰላሜን ÷
ቸርነትንና ፡ ምሕረትን ÷ ከዚህ ፡ ሕዝብ ፡ አስ
ወግጃለሁና ፡ ልቅሶ ፡ ወዳለበት ፡ ቤት ፡ አት
ግባ ÷ ታለቅስም ፡ ታዝንም ፡ ዘንድ ፡ አትሂድ ።
፮ ታላላቆችና ፡ ታናናሾች ፡ በዚህች ፡ ምድር ፡
ይሞታሉ ፤ አይቀበሩም ፡ ሰዎችም ፡ አያለቅሱ
ላቸውም ፡ ስለ ፡ እነርሱም ፡ ገላን ፡ አይነጩላ
፯ ቸውም ፡ ራስንም ፡ አይላጩላቸውም ፤ ሰዎ
ችም ፡ ስለ ፡ ሞቱት ፡ ለማጽናናት ፡ የእዝን ፡
እንጀራ ፡ አይቈርሱላቸውም ÷ ስለ ፡ አባታቸ
ውና ፡ ስለ ፡ እናታቸውም ፡ የመጽናናት ፡
፰ ጽዋ ፡ አያጠጡአቸውም ። ትበላና ፡ ትጠጣ ፡
ዘንድ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ለመቀመጥ ፡ ወደ ፡
፱ ግብዣ ፡ ቤት ፡ አትግባ ። የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላልና ፡— እነሆ ÷ በዓይናችሁ ፡ ፊት ፡ በዘመና
ችሁም ፡ የእልልታን ፡ ድምፅና ፡ የደስታን ፡
ድምፅ ፡ የወንድ ፡ ሙሽራን ፡ ድምፅና ፡ የሴት ፡
ሙሽራን ፡ ድምፅ ፡ ከዚህ ፡ ስፍራ ፡ አስቀራለሁ ።
፲ ለዚህም ፡ ሕዝብ ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ በተ
ናገርህ ፡ ጊዜ ፡— ይህን ፡ ሁሉ ፡ ታላቅ ፡ የሆነ ፡
ክፉ ፡ ነገርን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናገ
ረብን ? በደላችንስ ፡ ምንድር ፡ ነው ? በአምላ
ካችንስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ የሠራነው ፡
፲፩ ኃጢአታችን ፡ ምንድር ፡ ነው ? ቢሉህ ÷ አንተ ፡
እንዲህ ፡ ትላቸዋለህ ፡— አባቶቻችሁ ፡ እኔን ፡
ስለ ፡ ተዉ ፡ ነው ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ÷
ሌሎችንም ፡ አማልክት ፡ ተከተሉ ፡ አመለኩአ
ቸውም ፡ ሰገዱላቸውም ÷ እነርሱም ፡ ትተው

፲፪ ፡ ኛል ፡ ሕጌንም ፡ አልጠበቁም ፤ እናንተም ፡ ከአ
በቶቻችሁ ፡ ይልቅ ፡ ክፉ ፡ አድርጋችኋል ፤ እነ
ሆም ፡ ሁላችሁ ፡ እንደ ፡ ክፉ ፡ ልባችሁ ፡ እል
ከኝነት ፡ ሄዳችኋል ፡ እኔንም ፡ አልሰማችሁም ።
፲፫ ፡ ስለዚህ ፡ ከዚህች ፡ ምድር ፡ እናንተና ፡ አባቶቻ
ችሁ ፡ ወዳላወቃችኋት ፡ ምድር ፡ እጥላችኋለሁ ፤
ምሕረትንም ፡ አላደርግላችሁምና ፡ በዚያ ፡ ሌሎ
ችን ፡ አማልክት ፡ ቀንና ፡ ሌሊት ፡ ታመልካላ
ችሁ ።
፲፬ ፡ ስለዚህ ፡ እነሆ ፡— የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡
ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ያወጣ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብ
ሔርን ! ዳግመኛ ፡ የማይባልበት ፡ ዘመን ፡ ይመ
፲፭ ፡ ጣል ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ነገር ፡ ግን ፡—
የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ከሰሜን ፡ ምድር ፡ ካሳደ
ዳቸውም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ያወጣ ፡ ሕያው ፡
እግዚአብሔርን ! ይባላል ፤ እኔም ፡ ለአባቶቻ
ቸው ፡ ወደ ፡ ሰጠኋት ፡ ወደ ፡ ምድራቸው ፡ እመ
ልሳቸዋለሁ ።
፲፮ ፡ እነሆ ፡ ብዙ ፡ ዓሣ ፡ አጥማጆችን ፡ እሰድ
ዳለሁ ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፡ እነርሱም ፡
ያጠምዱአቸዋል ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ብዙ ፡ አዳ
ኞችን ፡ እሰድዳለሁ ፡ እነርሱም ፡ ከየተራራ
ውና ፡ ከየኮረብታው ፡ ሁሉ ፡ ከየድንጋዩም ፡
፲፯ ፡ ስንጣቂ ፡ ውስጥ ፡ ያድኑአቸዋል ። ዓይኔ ፡ በመ
ንገዳቸው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነው ፤ ከፊቴም ፡ አልተ
ሰወሩም ፡ ኃጢአታቸውም ፡ ከዓይኔ ፡ አልተሸ
፲፰ ፡ ሸገም ። ምድሬንም ፡ በተጠሉ ፡ በጣዖቶቻ
ቸው ፡ ሬሳዎች ፡ አርክሰዋልና ፡ ርስቴንም ፡
አስጸያፊ ፡ በሆኑ ፡ ነገሮች ፡ሞልተዋልና ፡ አስ
ቀድሜ ፡ የበደላቸውንና ፡ የኃጢአታቸውን ፡
ዕዳ ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ እከፍላቸዋለሁ ።
፲፱ ፡ አቤቱ ፡ ኃይሌ ፡ አምባዬ ፡ በመከራም ፡ ቀን ፡
መጠጊያዬ ፡ ሆይ ፡ ከምድር ፡ ዳርቻ ፡ አሕዛብ ፡
ወደ ፡ አንተ ፡ መጥተው ፡— በእውነት ፡ አባቶ
ቻችን ፡ ውሸትንና ፡ ከንቱን ፡ ነገር ፡ የማይረባ
፳ ፡ ቸውንም ፡ ወርሰዋል ፡ ይላሉ ። በውኑ ፡ ሰው ፡
አማልክት ፡ ያልሆኑትን ፡ ለራሱ ፡ አማልክትን ፡
አድርጎ ፡ ይሠራልን ?
፳፩ ፡ ስለዚህ ፡ እነሆ ፡ አስታውቃቸዋለሁ ፡
በዚህች ፡ ጊዜ ፡ እጄንና ፡ ኃይሌን ፡ አስታውቃ
ቸዋለሁ ፤ እነርሱም ፡ ስሜ ፡ እግዚአብሔር ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ ያውቃሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ ፡ የይሁዳ ፡ ኃጢአት ፡ በብረት ፡ ብርዕና ፡ በተ
ሾለ ፡ ዕብነ ፡ አልማዝ ፡ ተጽፎአል ፤ በልባቸው ፡
ጽላትና ፡ በመሠዊያቸው ፡ ቀንዶች ፡ ተቀርጾ
፪ ፡ አል ። ልጆቻቸውም ፡ ከለመለሙ ፡ ዛፎች ፡
በታችና ፡ በረዘሙት ፡ ኮረብቶች ፡ ላይ ፡ ያሉትን ፡
መሠዊያቸውንና ፡ የማምለኪያ ፡ ዐፀዳቸውን ፡
፫ ፡ ያስባሉ ። በሜዳ ፡ ያለው ፡ ተራራዬ ፡ ሆይ ፡
ባለጠግነትህንና ፡ መዝገብህን ፡ ሁሉ ፡ የኮረብ
ታውን ፡ መስገጃዎችህም ፡ ስለ ፡ ኃጢአት ፡ በድ
፬ ፡ ንበሮችህ ፡ ሁሉ ፡ ለመበዝበዝ ፡ እሰጣለሁ ። አን
ተም ፡ የሰጠሁህን ፡ ርስት ፡ ትለቅቃለህ ፡ ለዘላ
ለምም ፡ በማታውቃትም ፡ ምድር ፡ ለጠላቶቻ
ችሁ ፡ ባሪያ ፡ አደርግሃለሁ ፤ ለዘላለም ፡ የሚነ
ድደውን ፡ እሳት ፡ በቍጣዬ ፡ አንድዳችኋልና ።
፭ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በሰው ፡
የሚታመን ፡ ሥጋ ፡ ለበሹንም ፡ ክንዱ ፡ የሚያ
ደርግ ፡ ልቡም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የሚመለስ ፡
፮ ፡ ሰው ፡ ርጉም ፡ ነው ። በምድረ ፡ በዳ ፡ እንዳለ ፡
ቍጥቋጦ ፡ ይሆናል ፡ መልካምም ፡ በመጣ ፡
ጊዜ ፡ አያይም ፤ ሰውም ፡ በሌለበት ፡ ጨው ፡
ባለበት ፡ ምድር ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ በደረቅ ፡
፯ ፡ ስፍራ ፡ ይቀመጣል ። በእግዚአብሔር ፡ የታ
መነ ፡ እምነቱም ፡ እግዚአብሔር ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡
፰ ፡ ቡሩክ ፡ ነው ። በውኃ ፡ አጠገብ ፡ እንደ ፡ ተተ
ከለ ፡ በወንዝም ፡ ዳር ፡ ሥሩን ፡ እንደሚዘረጋ ፡
ሙቀትም ፡ ሲመጣ ፡ እንደማይፈራ ፡ ቅጠሉም ፡
እንደሚለመልም ፡ በድርቅ ፡ ዓመትም ፡ እንደ
ማይሠጋ ፡ ፍሬውንም ፡ እንደማያቋርጥ ፡ ዛፍ ፡
ይሆናል ።
፱ ፡ የሰው ፡ ልብ ፡ ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ተንኰለኛ ፡
እጅግም ፡ ክፉ ፡ ነው ፤ ማንስ ፡ ያውቀዋል ?
፲ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሰው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡
መንገዱ ፡ እንደ ፡ ሥራው ፡ ፍሬ ፡ እሰጥ ፡ ዘንድ ፡
ልብን ፡ እመረምራለሁ ፡ ኵላሊትንም ፡ እፈት
፲፩ ፡ ናለሁ ። ያልወለደችውን ፡ እንደምታቀፍ ፡
ቆቅ ፡ እንዲሁ ፡ በቅን ፡ ሳይሆን ፡ ባለጠግነትን ፡
የሚሰበስብ ፡ ሰው ፡ ነው ፤ በእኩሌታ ፡ ዘመኑ ፡
ይተወዋል ፡ በፍጻሜውም ፡ ሰነፍ ፡ ይሆናል ።
፲፪ ፡ የመቅደሳችን ፡ ስፍራ ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡
፲፫ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ የክብር ፡ ዙፋን ፡ ነው ። አቤቱ ፡
የእስራኤል ፡ ተስፋ ፡ ሆይ ፡ የሚተዉህ ፡ ሁሉ ፡
ያፍራሉ ፤ ከአንተም ፡ የሚለዩ ፡ የሕይወትን ፡
ውኃ ፡ ምንጭ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትተዋልና ፡
፲፬ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ይጻፋሉ ። አቤቱ ፡ ፈውሰኝ ፡
እኔም ፡ እፈወሳለሁ ፤ አድነኝ ፡ እኔም ፡ እድናለሁ ፤
፲፭ ፡ አንተ ፡ ምስጋናዬ ፡ ነህና ። እነሆ ፡— የእግዚአብ
ሔር ፡ ቃል ፡ ወዴት ፡ አለች ? አሁን ፡ ትምጣ ፡
፲፮ ፡ ይሉኛል ። እኔም ፡ አንተን ፡ ተከትዬ ፡ እረኛ ፡
ከመሆን ፡ አልቸኰልሁም ፡ የመከራንም ፡ ቀን ፡
አልወደድሁም ፤ አንተ ፡ ታውቃለህ ፤ ከከንፈሬ ፡
፲፯ ፡ የወጣው ፡ በፊትህ ፡ ነበረ ። ለማስፈራራት ፡
አትሁንብኝ ፤ በመከራ ፡ ቀን ፡ አንተ ፡ መጠጊ
፲፰ ፡ ያዬ ፡ ነህ ። አሳዳጆቼ ፡ ይፈሩ ፡ እኔ ፡ ግን ፡ አል
ፈር ፤ እነርሱ ፡ ይደንግጡ ፡ እኔ ፡ ግን ፡ አልደን
ግጥ ፤ ክፉንም ፡ ቀን ፡ አምጣባቸው ፡ በሁለት ፡
እጥፍ ፡ ጥፋት ፡ አጥፋቸው ።
፲፱ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይለኛል ፡— ሂድ ፡
የይሁዳም ፡ ነገሥታት ፡ በሚገቡበትና ፡ በሚወ
ጡበት ፡ በሕዝቡ ፡ ልጆች ፡ በር ፡ በኢየሩሳሌ
፳ ፡ ምም ፡ በሮች ፡ ሁሉ ፡ ቁም ፤ እንዲህም ፡ በላ
ቸው ፡— በእነዚህ ፡ በሮች ፡ የምትገቡ ፡ እና
ንተ ፡ የይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ይሁዳም ፡ ሁሉ ፡
በኢየሩሳሌምም ፡ የምትኖሩ ፡ ሁሉ ፡ የእግ
፳፩ ፡ ዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስሙ ። እግዚአብሔር ፡

እንዲህ ፡ ይላል ፡— ለራሳችሁ ፡ ተጠንቀቁ ፥
በሰንበትም ፡ ቀን ፡ ሸክም ፡ አትሸከሙ ፥ በኢ
፳፪፤ የሩሳሌምም ፡ በሮች ፡ አታግቡ ፥ ከቤቶቻች
ሁም ፡ በሰንበት ፡ ቀን ፡ ሸክምን ፡ አታውጡ ፥
ሥራንም ፡ ሁሉ ፡ አትሥሩበት ፤ አባቶቻችሁ
ንም ፡ እንዳዘዝሁ ፡ የሰንበትን ፡ ቀን ፡ ቀድሱ ።
፳፫፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ አልሰሙም ፡ ጆሮአቸውን ፡ አላ
ዘነበሉም ፥ እንዳይሰሙና ፡ እንዳይገሠጹም ፡
አንገታቸውን ፡ አደነደኑ ።
፳፬፤ እኔን ፡ ፈጽሞ ፡ ብትሰሙ ፥ ይላል ፡ እግዚአ
ብሔር ፥ በሰንበትም ፡ ቀን ፡ በዚህች ፡ ከተማ ፡
በሮች ፡ ሸክም ፡ ባታገቡ ፥ የሰንበትንም ፡ ቀን ፡
ብትቀድሱ ፡ ሥራንም ፡ ሁሉ ፡ ባትሠሩበት ፥
፳፭፤ በዳዊት ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ የሚቀመጡ ፡ ነገሥታ
ትና ፡ መሳፍንት ፡ በሰረገሎችና ፡ በፈረሶች ፡
ላይ ፡ እየተቀመጡ ፡ በዚህች ፡ ከተማ ፡ በሮች ፡
ይገባሉ ፤ እነርሱና ፡ መሳፍንቶቻቸው ፡ የይሁ
ዳም ፡ ሰዎች ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ የሚቀመጡ ፡
ይገባሉ ፥ ይህችም ፡ ከተማ ፡ ለዘላለም ፡ የሰው ፡
፳፮፤ መኖሪያ ፡ ትሆናለች ። የሚቃጠለውን ፡ መሥ
ዋዕትና ፡ ሌላ ፡ መሥዋዕትን ፡ የእህሉንም ፡ ቍር
ባን ፡ ዕጣኑንም ፡ የምስጋናውንም ፡ መሥዋዕት ፡
ይዘው ፡ ከይሁዳ ፡ ከተሞች ፡ ከኢየሩሳሌምም ፡
ዙሪያ ፡ ከብንያምም ፡ አገር ፡ ከቈላውም ፡ ከደ
ጋውም ፡ ከደቡብም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
፳፯፤ ቤት ፡ ይመጣሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ የሰንበትን ፡ ቀን ፡
እንድትቀድሱ ፥ በሰንበትም ፡ ቀን ፡ ሸክምን ፡
ተሸክማችሁ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በሮች ፡ እንዳት
ገቡ ፡ የነገርኋችሁን ፡ ባትሰሙኝ ፥ በበሮችዋ ፡
ላይ ፡ እሳትን ፡ አነድዳለሁ ፥ የኢየሩሳሌምንም ፡
አዳራሾች ፡ ትበላለች ፥ አትጠፋም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩፤፪፤ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡
የመጣ ፡ ቃል ፥ እንዲህም ፡ አለው ፡— ተነሥ
ተህ ፡ ወደ ፡ ሸክላ ፡ ሠሪው ፡ ቤት ፡ ውረድ ፥
፫፤ በዚያም ፡ ቃሌን ፡ አሰማሃለሁ ። ወደ ፡ ሸክላ ፡
ሠሪው ፡ ቤትም ፡ ወረድሁ ፥ እነሆም ፥ ሥራ
ውን ፡ በመንኰራኵር ፡ ላይ ፡ ይሠራ ፡ ነበር ።
፬፤ ከጭቃም ፡ ይሠራው ፡ የነበረ ፡ ዕቃ ፡ በሸክላ ፡
ሠሪው ፡ እጅ ፡ ተበላሸ ፥ ሸክላ ፡ ሠሪውም ፡ እንደ ፡
ወደደ ፡ መልሶ ፡ ሌላ ፡ ዕቃ ፡ አድርጎ ፡ ሠራው ።
፭፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፮፤ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ። የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥
ይህ ፡ ሸክላ ፡ ሠሪ ፡ እንደሚሠራ ፡ በውኑ ፡ እኔ ፡
በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ መሥራት ፡ አይቻለኝምን ?
እነሆ ፥ ጭቃው ፡ በሸክላ ፡ ሠሪ ፡ እጅ ፡ እንዳለ ፥
፯፤ እንዲሁ ፡ እናንተ ፡ በእኔ ፡ እጅ ፡ አላችሁ ። ስለ ፡
ሕዝብ ፡ ስለ ፡ መንግሥትም ፡ እነቅል ፡ አፈር
ስም ፡ አጠፋም ፡ ዘንድ ፡ በተናገርሁ ፡ ጊዜ ፥
፰፤ ይህ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ የተናገርሁበት ፡ ሕዝብ ፡ ከክ
ፋቱ ፡ ቢመለስ ፥ እኔ ፡ አደርግበት ፡ ዘንድ ፡ካሰብ
፱፤ ሁት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እጸጸታለሁ ። ስለ ፡ ሕዝብም ፡
ስለ ፡ መንግሥትም ፡ እሠራውና ፡ እተክለው ፡
፲፤ ዘንድ ፡ በተናገርሁ ፡ ጊዜ ፥ በፊቴ ፡ ክፉን ፡ ነገር ፡
ቢያደርግ ፡ ቃሌንም ፡ ባይሰማ ፥ እኔ ፡ አደርግ
ለት ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ተናገርሁት ፡ መልካም ፡ ነገር ፡
፲፩፤ እጸጸታለሁ ። አሁን ፡ እንግዲህ ፡ ለይሁዳ ፡
ሰዎችና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለሚቀመጡ ፡— እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ፥ ክፉ ፡
ነገር ፡ እፈጥርባችኋለሁ ፥ አሳብንም ፡ አስብባች
ኋለሁ ፤ አሁንም ፡ ሁላችሁ ፡ ከክፉ ፡ መንገዳ
ችሁ ፡ ተመለሱ ፥ መንገዳችሁንና ፡ ሥራችሁ
፲፪፤ ንም ፡ አቅኑ ፡ ብለህ ፡ ተናገራቸው ። እነርሱ ፡
ግን ፡— እንጨክናለን ፤ አሳባችንን ፡ ተከትለን ፡
እንሄዳለን ፡ ሁላችንም ፡ እንደ ፡ ክፉው ፡ ልባ
ችን ፡ እልከኝነት ፡ እናደርጋለን ፡ አሉ ።
፲፫፤ ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
በአሕዛብ ፡ መካከል ፡— እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ማን ፡
ሰምቶአል ? ብላችሁ ፡ ጠይቁ ። የእስራኤል ፡
ድንግል ፡ በጣም ፡ የሚያስደነግጠውን ፡ ነገር ፡
፲፬፤ አድርጋለች ። በውኑ ፡ የሊባኖስ ፡ በረዶ ፡ የም
ድረ ፡ በዳውን ፡ ድንጋይ ፡ ይተዋልን ? ወይስ ፡
ከሩቅ ፡ የምትመጣው ፡ ቀዝቃዛይቱ ፡ ፈሳሽ ፡
፲፭፤ ውኃ ፡ ትደርቃለችን ? ሕዝቤ ፡ ግን ፡ ረስተው
ኛል ፡ ለከንቱ ፡ ነገርም ፡ ዐጥነዋል ፤ ከመንገዱም ፡
ተሰናክለዋል ፡ ከቀድሞውም ፡ ጐዳና ፡ ርቀው ፡
ወዳልተሠራው ፡ ወደ ፡ ጠማማው ፡ መንገድ ፡
፲፮፤ ፈቀቅ ፡ ብለዋል ። ምድራቸውን ፡ ለመደነቂ
ያና ፡ ለዘላለም ፡ ማፍዋጫ ፡ አድርገዋል ፤ የሚ
ያልፍበት ፡ ሁሉ ፡ ይደነቃል ፥ ራሱንም ፡ ያነቃ
፲፯፤ ንቃል ። በጠላት ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ምሥራቅ ፡
ነፋስ ፡ እበትናቸዋለሁ ፥ በጥፋታቸውም ፡ ቀን ፡
ጀርባዬን ፡ እንጂ ፡ ፊቴን ፡ አላሳያቸውም ።
፲፰፤ እነርሱም ፡— ሕግ ፡ ከካህን ፥ ምክርም ፡ ከጠ
ቢብ ፥ ቃልም ፡ ከነቢይ ፡ አይጠፋምና ፡ ኑ ፥
በኤርምያስ ፡ ላይ ፡ አሳብን ፡ እናስብ ። ኑ ፥ በም
ላስ ፡ እንምታው ፥ ቃሉንም ፡ ሁሉ ፡ አናድ
ምጥ ፡ አሉ ።
፲፱፤ አቤቱ ፥ አድምጠኝ ፥ የከርከሬንም ፡ ቃል ፡
፳፤ ስማ ። ለነፍሴ ፡ ጕድጓድ ፡ ቈፍረዋልና ፡ በውኑ ፡
በመልካም ፡ ፋንታ ፡ ክፉ ፡ ይመለሳልን ? ስለ ፡
እነርሱ ፡ በመልካም ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ ቍጣህ
ንም ፡ ከእነርሱ ፡ እመልስ ፡ ዘንድ ፡ በፊትህ ፡
፳፩፤ እንደ ፡ ቆምሁ ፡ አስብ ። ስለዚህ ፡ ልጆቻቸውን ፡
ለራብ ፡ ስጥ ፥ ለሰይፍም ፡ እጅ ፡ አሳልፈህ ፡ ስጣ
ቸው ፥ ሚስቶቻቸውም ፡ የወላድ ፡ መካንና ፡
መበለቶች ፡ ይሁኑ ፥ ወንዶቻቸውም ፡ በሞት ፡
ይጥፉ ፥ ጕልማሶቻቸውም ፡ በሰልፍ ፡ ጊዜ ፡
፳፪፤ በሰይፍ ፡ ይመቱ ። ሊይዙኝ ፡ ጕድጓድ ፡ ቆፍረ
ዋልና ፥ ለእግሮቼም ፡ ወጥመድ ፡ ሸሽገዋልና ፡
ድንገት ፡ በላያቸው ፡ ጭፍራ ፡ በመጣህ ፡ ጊዜ ፡
፳፫፤ ከቤታቸው ፡ ጩኸት ፡ ይሰማ ። አንተ ፡ ግን ፥
አቤቱ ፥ ይገድሉኝ ፡ ዘንድ ፡ በላዬ ፡ የመከሩ
ትን ፡ ምክር ፡ ሁሉ ፡ ታውቃለህ ፤ በደላቸውን ፡
ይቅር ፡ አትበል ፥ ኃጢአታቸውንም ፡ ከፊትህ ፡
አትደምስስ ፤ በፊትህም ፡ ይውደቁ ፥ በቍጣህ ፡
ጊዜ ፡ እንዲሁ ፡ አድርግባቸው ።

## ምዕራፍ፡፲፱።

፩ እግዚአብሔርም፡እንዲህ፡አለኝ፡— ሂድ÷
ከሸክላ፡ሠሪ፡ገምቦ፡ግዛ÷ከሕዝቡም፡ሽማ
ግሌዎችና፡ከካህናት፡ሽማግሌዎች፡ከአንተ፡
፪ ጋር፡ውሰድ፤ በካርሲት፡በር፡መግቢያ፡አጠ
ገብ፡ወዳለው፡ወደ፡ሄኖም፡ልጅ፡ሸለቆ፡
ሂድ÷በዚያም፡የምነግርህን፡ቃል፡ተናገር÷
፫ እንዲህም፡በል፡— የይሁዳ፡ነገሥታትና፡በኢ
የሩሳሌም፡የምትኖሩ፡ሆይ÷የእግዚአብሔ
ርን፡ቃል፡ስሙ፤ የእስራኤል፡አምላክ፡የሠ
ራዊት፡ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡—
የሰማውን፡ሰው፡ጆሮ፡ጭው፡የሚያደርግ፡
ክፉ፡ነገር÷እነሆ÷በዚህ፡ስፍራ፡አመጣለሁ።
፬ ትተውኛልና÷ይህንም፡ስፍራ፡እንግዳ፡አድ
ርገውታልና÷እነርሱና፡አባቶቻቸውም፡ለማ
ያውቋቸው፡ለሌሎች፡አማልክት፡ዐጥነዋ
ልና÷የይሁዳም፡ነገሥታት፡ይህን፡ስፍራ፡
፭ በንጹሕ፡ደም፡ሞልተዋልና÷እኔም፡ያላዘ
ዝሁትን፡ያልተናገርሁትንም፡ወደ፡ልቤም፡
ያልገባውን÷የሚቃጠለውን፡መሥዋዕት፡
አድርገው፡ለበኣል፡ልጆቻቸውን፡በእሳት፡
ያቃጥሉ፡ዘንድ፡የበኣልን፡የኮረብታውን፡
፮ መስገጃዎች፡ሠርተዋልና፡ስለዚህ÷እነሆ÷
ይህ፡ስፍራ፡የእርድ፡ሸለቆ፡ይባላል፡እንጂ፡
ቶፌት፡ወይም፡የሄኖም፡ልጅ፡ሸለቆ፡ዳግ
መኛ፡የማይባልበት፡ዘመን፡ይመጣል÷ይላል፡
፯ እግዚአብሔር። በዚህም፡ስፍራ፡የይሁዳንና፡
የኢየሩሳሌምን፡ምክር፡አፈርሳለሁ÷በጠላቶ
ቻቸውም፡ፊት፡በሰይፍና፡ነፍሳቸውን፡በሚ
ሹት፡እጅ፡እጥላቸዋለሁ÷ሬሳቸውንም፡ለሰ
ማይ፡ወፎችና፡ለምድር፡አራዊት፡መብል፡
፰ አድርጌ፡እሰጣለሁ። ይህችንም፡ከተማ፡ለመ
ደነቂያና፡ለማፍዋጫ፡አደርጋታለሁ፤የሚያል
ፍባትም፡ሁሉ፡ስለ፡ተደረገባት፡መቅሠፍት፡
ሁሉ፡ይደነቃል፡ከንፈሩንም፡ይመጥጣል።
፱ የወንዶችና፡የሴቶች፡ልጆቻቸውንም፡ሥጋ፡
አበላቸዋለሁ÷ሁሉም፡ጠላቶቻቸውና፡ነፍሳ
ቸውን፡የሚሹት፡በሚያስጨንቋቸው፡ጭን
ቀትና፡መከበብ፡የባልንጀሮቻቸውን፡ሥጋ፡
ይበላሉ።
፲ ገምቦውንም፡ከአንተ፡ጋር፡በሚሄዱ፡ሰዎች፡
፲፩ ፊት፡ትሰብራለህ÷እንዲህም፡ትላቸዋለህ፡—
የሠራዊት፡ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡
ይላል፡— የሸክላ፡ሠሪው፡ዕቃ፡እንደሚሰበ
በር፡ደግሞም፡ይጠገን፡ዘንድ፡እንደማይቻል÷
እንዲሁ፡ይህን፡ሕዝብና፡ይህችን፡ከተማ፡እሰ
ብራለሁ፤ የሚቀብሩበትም፡ስፍራ፡ሌላ፡የለ
፲፪ ምና፡በቶፌት፡ይቀብራሉ። እንዲሁ፡በዚህ፡
ስፍራና፡በሚኖሩበት፡ላይ፡አደርጋለሁ÷
ይላል፡እግዚአብሔር÷ይህችንም፡ከተማ፡
፲፫ እንደ፡ቶፌት፡አደርጋለሁ። የረከሱትም፡የኢ
የሩሳሌም፡ቤቶችና፡የይሁዳ፡ነገሥታት፡
ቤቶች÷እነዚያ፡በሰገነታቸው፡ላይ፡ለሰማይ
ሠራዊት፡ሁሉ፡ያጠኑባቸው፡ለሌሎችም፡
አማልክት፡የመጠጥን፡ቍርባን፡ያፈሰሱብ
ቸው፡ቤቶች፡ሁሉ÷እንደ፡ቶፌት፡ስፍራ፡
ይሆናሉ።
፲፬ ኤርምያስም፡እግዚአብሔር፡ትንቢት፡ሊና
ገር፡ወደዚያ፡ልኮት፡ከነበረው፡ስፍራ፡ከቶ
ፌት፡መጣ÷በእግዚአብሔርም፡ቤት፡አደባ
፲፭ ባይ፡ቆሞ፡ለሕዝብ፡ሁሉ፡— የእስራኤል፡
አምላክ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡—
ቃሌን፡እንዳይሰሙ፡አንገታቸውን፡አደንድ
ነዋልና፡እነሆ÷በዚህች፡ከተማና፡በመንደሮ
ችዋ፡ሁሉ፡ላይ፡የተናገርሁባትን፡ክፉ፡ነገር፡
ሁሉ፡አመጣለሁ።

## ምዕራፍ፡፳።

፩ በእግዚአብሔርም፡ቤት፡የተሾመው፡አለቃ፡
የካህኑ፡የኢሜር፡ልጅ፡ጳስኮር፡ኤርምያስ፡
፪ በዚህ፡ነገር፡ትንቢት፡ሲናገር፡ሰማ። ጳስኮ
ርም፡ነቢዩን፡ኤርምያስን፡መታው÷በእግ
ዚአብሔርም፡ቤት፡በነበረው፡በላይኛው፡
በብንያም፡በር፡ባለው፡በእግር፡ግንድ፡
፫ ውስጥ፡አኖረው። በነጋውም፡ጳስኮር፡ኤር
ምያስን፡ከግንድ፡ውስጥ፡አወጣው። ኤርምያ
ስም፡እንዲህ፡አለው፡— እግዚአብሔር፡ስም
ህን፡— ማጎርሚሳቢብ፡እንጂ፡ጳስኮር፡ብሎ፡
፬ አይጠራህም። እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላ
ልና፡— እነሆ÷ለራስህና፡ለወዳጆችህ፡ሁሉ፡
ፍርሃት፡አደርግሃለሁ፤ እነርሱም፡በጠላቶቻ
ቸው፡ሰይፍ፡ይወድቃሉ፡ዓይኖችህም፡
ያያሉ፤ ይሁዳንም፡ሁሉ፡በባቢሎን፡ንጉሥ፡
እጅ፡አሳልፌ፡እሰጣለሁ÷እርሱም፡ወደ፡
ባቢሎን፡ያፈልሳቸዋል፡በሰይፍም፡ይገድላ
፭ ቸዋል። የዚህችንም፡ከተማ፡ባለጠግነት፡
ሁሉ፡ጥሪትዋንም፡ሁሉ፡ክብርዋንም፡ሁሉ፡
የይሁዳንም፡ነገሥታት፡መዝገብ፡ሁሉ፡በጠ
ላቶቻቸው፡እጅ፡አሳልፌ፡እሰጣለሁ÷እነር
ሱም፡ይበዘብዙአቸዋል፡ይዘውም፡ወደ፡ባቢ
፮ ሎን፡ያፈልሱአቸዋል። አንተም÷ጳስኮር፡
ሆይ÷በቤትህም፡የሚኖሩት፡ሁሉ፡ተማርካ
ችሁ፡ትሄዳላችሁ፤ አንተም፡በሐሰትም፡ትን
ቢት፡የተናገርህላቸው፡ወዳጆችህ፡ሁሉ፡
ወደ፡ባቢሎን፡ትገባላችሁ÷በዚያም፡ትሞ
ታላችሁ÷በዚያም፡ትቀበራላችሁ።
፯ አቤቱ÷አታለልኸኝ፡እኔም፡ተታለልሁ÷
ከእኔም፡በረታህ፡አሸነፍህም፤ ቀኑን፡ሁሉ፡
መሳቂያ፡ሆኛለሁ÷ሁሉም፡ያላግጡብኛል።
፰ በተናገርሁ፡ቍጥር፡እጮኻለሁ፤ግፍና፡ጥፋት፡
ብዬ፡እጮኻለሁ፤የእግዚአብሔር፡ቃል፡ቀኑን፡
፱ ሁሉ፡ስድብና፡ዋዛ፡ሆኖብኛልና። እኔም፡—
የእግዚአብሔርን፡ስም፡አላነሣም÷ከእንግ
ዲህ፡ወዲህም፡በስሙ፡አልናገርም፡ብል÷
በአጥንቶቼ፡ውስጥ፡እንደ፡ገባ፡እንደሚነድድ፡
እሳት፡ያለ፡በልቤ፡ሆነብኝ፤ ደከምሁ÷መሸ
፲ ከምም፡አልቻልሁም። የብዙ፡ሰዎችን፡ስድብ፡

ሰምቻለሁ፥ ማስፈራራትም፡ ከብበኛል። መውደቄን፡ የሚጠብቁ፡ የሰላሜ፡ ሰዎች፡ ሁሉ፡— ምናልባት፡ ይታለል፡ እንደ፡ ሆነ፥ እናሸንፈውም፡ እንደ፡ ሆነ፥ እርሱንም፡ እንበቀል፡ እንደ፡ ሆነ፥ ክሰሱት፡ እኛም፡ እንከስሰዋለን፡ ይላሉ። ፲፩ እግዚአብሔር፡ ግን፡ እንደ፡ ኃያልና፡ እንደ፡ ጨካኝ፡ ከእኔ፡ ጋር፡ ነው፤ ስለዚህ፡ አሳዳጆቼ፡ ይሰናከላሉ፡ አያሸንፉም፤ አይከናወንላቸውምና፡ በጽኑ፡ እፍረት፡ ያፍራሉ፥ ለዘላለምም፡ በማይረሳ፡ ጕስቍልና፡ ይጐሰቍላሉ። ፲፪ አቤቱ፥ ጻድቅን፡ የምትመረምር፡ ኵላሊትንና፡ ልብን፡ የምትመለከት፡ የሠራዊት፡ ጌታ፡ ሆይ፥ ክርክሬን፡ ገልጬልሃለሁና፡ በቀልህን፡ በላያቸው፡ ላይ። ፲፫ ለእግዚአብሔር፡ ዘምሩ፡ እግዚአብሔርንም፡ አመስግኑ፤ የችግረኛውን፡ ነፍስ፡ ከክፉ፡ አድራጊዎች፡ እጅ፡ አድኖአልና።

፲፬ የተወለድሁበት፡ ቀን፡ የተረገመች፡ ትሁን፤ እናቴ፡ እኔን፡ የወለደችበት፡ ቀን፡ የተባረከች፡ አትሁን። ፲፭ ወንድ፡ ልጅ፡ ተወልዶልሃል፡ ብሎ፡ ለአባቴ፡ የምሥራች፡ ነግሮ፡ ደስ፡ ያሰኘው፡ ሰው፡ የተረገመ፡ ይሁን። ፲፮ ያም፡ ሰው፡ እግዚአብሔር፡ ሳይጸጸት፡ እንደ፡ ገለበጣቸው፡ ከተሞች፡ ይሁን፥ በማለዳም፡ ልቅሶን፡ በቀትርም፡ ጩኸትን፡ ይስማ፤ ፲፯ እናቴ፡ መቃብር፡ ትሆነኝ፡ ዘንድ፡ ማኅፀንዋም፡ ዘወትር፡ ይዘኝ፡ ያቆይ፡ ዘንድ፡ በማኅፀን፡ ውስጥ፡ አልገደለኝምና። ፲፰ ድካምንና፡ ጣርን፡ አይ፡ ዘንድ፡ ዘመኔም፡ በእፍረት፡ ታልቅ፡ ዘንድ፡ ስለ፡ ምን፡ ከማኅፀን፡ ወጣሁ?

## ምዕራፍ፡ ፳፩።

፩ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ወደ፡ ኤርምያስ፡ የመጣ፡ ቃል፡ ይህ፡ ነው። ፪ ይህም፡ የሆነው፡ ንጉሡ፡ ሴዴቅያስ፡— የባቢሎን፡ ንጉሥ፡ ናቡከደነፆር፡ ይወጋናልና፡ ስለ፡ እኛ፥ እባክህ፥ እግዚአብሔርን፡ ጠይቅ፤ ከእኛም፡ ይመለስ፡ ዘንድ፡ ምናልባት፡ እግዚአብሔር፡ ከእኛ፡ ጋር፡ እንደ፡ ተአምራቱ፡ ሁሉ፡ ያደርግ፡ ይሆናል፡ ብሎ፡ የመልክያን፡ ልጅ፡ ጳስኮርንና፡ ካህኑን፡ የመዕሤያን፡ ልጅ፡ ሶፎንያስን፡ ወደ፡ ኤርምያስ፡ በላከ፡ ጊዜ፡ ነው።

፫ ኤርምያስም፡ እንዲህ፡ አላቸው፡— ሴዴቅያስን፡ እንዲህ፡ በሉት፡— ፬ የእስራኤል፡ አምላክ፡ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡— እነሆ፥ የባቢሎንን፡ ንጉሥ፡ በቅጥርም፡ ውጭ፡ የከበቡአችሁን፡ ከለዳውያንን፡ የምትወጉበትን፡ በእጃችሁ፡ ያለውን፡ ዕቃ፡ ጦራችሁን፡ እመልሰዋለሁ፥ እነዚያንም፡ ወደዚህች፡ ከተማ፡ ውስጥ፡ እሰበስባቸዋለሁ። ፭ እኔም፡ በተዘረጋች፡ እጅና፡ በብርቱ፡ ክንድ፥ በቍጣና፡ በመዓት፡ በታላቅም፡ መቅሠፍት፡ እወጋችኋለሁ። ፮ በዚህችም፡ ከተማ፡ የሚኖሩትን፡ ሁሉ፡ ሰዎችንና፡ እንስሶችን፡ እመታለሁ፥ በጽኑም፡ ቸነፈር፡ ይሞታሉ። ፯ ከዚህ፡ በኋላ፥ ይላል፡ እግዚአብሔር፥ የይሁዳን፡ ንጉሥ፡ ሴዴቅያስን፡ ከቸነፈርና፡ ከሰይፍ፡ ከራብም፡ በዚህች፡ ከተማ፡ የቀሩትንም፡ ባሪያዎቹንና፡ ሕዝቡን፡ በባቢሎን፡ ንጉሥ፡ በናቡከደነፆር፡ እጅ፡ በጠላቶቻቸውና፡ ነፍሳቸውንም፡ በሚሹት፡ እጅ፡ አሳልፌ፡ እሰጣቸዋለሁ፤ እርሱም፡ በሰይፍ፡ ስለት፡ ይመታቸዋል፤ አያዝንላቸውም፥ አይራራላቸውም፥ አይምራቸውም።

፰ ለዚህም፡ ሕዝብ፡ እንዲህ፡ በል፡— እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡— እነሆ፥ በፊታችሁ፡ የሕይወትን፡ መንገድና፡ የሞትን፡ መንገድ፡ አድርጌአለሁ። ፱ በዚህች፡ ከተማ፡ ውስጥ፡ የሚዘገይ፡ በሰይፍና፡ በራብ፡ በቸነፈርም፡ ይሞታል፤ ወጥቶ፡ ወደ፡ ከበቡአችሁ፡ ወደ፡ ከለዳውያን፡ የሚገባ፡ ግን፡ በሕይወት፡ ይኖራል፥ ነፍሱም፡ ምርኮ፡ ትሆንለታለች። ፲ ለመልካም፡ ሳይሆን፡ ለክፉ፡ ፊቴን፡ በዚህች፡ ከተማ፡ ላይ፡ አድርጌአለሁና፤ ለባቢሎን፡ ንጉሥ፡ እጅ፡ ትሰጣለች፥ እርሱም፡ በእሳት፡ ያቃጥላታል።

፲፩ የይሁዳ፡ ንጉሥ፡ ቤት፡ ሆይ፥ የእግዚአብሔርን፡ ቃል፡ ስሙ። ፲፪ የዳዊት፡ ቤት፡ ሆይ፥ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡— ስለ፡ ሥራችሁ፡ ክፋት፡ ቍጣዬ፡ እንደ፡ እሳት፡ እንዳይወጣና፡ ማንም፡ ሳያጠፋው፡ እንዳይነድድ፥ በማለዳ፡ ፍርድን፡ አድርጉ፡ የተበዘበዘውንም፡ ከአስጨናቂው፡ እጅ፡ አድኑ። ፲፫ እነሆ፥ በሸለቆው፡ ውስጥ፡ በሜዳ፡ ላይም፡ በለው፡ አምባ፡ የምትቀመጪ፡ ሆይ፥ እኔ፡ በአንቺ፡ ላይ፡ ነኝ፤ እናንተም፡— በእኛ፡ ላይ፡ የሚወርድ፡ ወይም፡ ወደ፡ መኖሪያችን፡ የሚገባ፡ ማን፡ ነው? የምትሉ፡ ሆይ፥ እኔ፡ በእናንተ፡ ላይ፡ ነኝ፤ ፲፬ እንደ፡ ሥራችሁም፡ ፍሬ፡ እቀጣችኋለሁ፤ በዱርዋም፡ ውስጥ፡ እሳትን፡ አነድዳለሁ፥ በዙሪያዋም፡ ያለውን፡ ሁሉ፡ ይበላል።

## ምዕራፍ፡ ፳፪።

፩ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ አለ፡— ወደ፡ ይሁዳ፡ ንጉሥ፡ ቤት፡ ውረድ፡ በዚያም፡ ይህን፡ ቃል፡ ተናገር፥ እንዲህም፡ በል፡— ፪ በዳዊት፡ ዙፋን፡ የምትቀመጥ፡ የይሁዳ፡ ንጉሥ፡ ሆይ፥ አንተና፡ ባሪያዎችህ፡ በእነዚህም፡ በሮች፡ የሚገቡ፡ ሕዝብህ፥ የእግዚአብሔርን፡ ቃል፡ ስሙ። ፫ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡— ፍርድንና፡ ጽድቅን፡ አድርጉ፡ የተበዘበዘውንም፡ ከአስጨናቂው፡ እጅ፡ አድኑ፤ መጻተኛውንና፡ ድሀ፡ አደጉን፡ መበለቲቱንም፡ አትበድሉ፥ አታምፁባቸውም፥ በዚህም፡ ስፍራ፡ ንጹሕ፡ ደምን፡ አታፍስሱ። ፬ ይህንንም፡ ነገር፡ ብታደርጉ፥ በዳዊት፡ ዙፋን፡ የሚቀመጡ፡ ነገሥታት፥ በሰረገሎችና፡ በፈረሶች፡ ላይ፡ ተቀምጠው፥ በዚህ፡ ቤት፡ በሮች፡ ይገባሉ፤ እርሱም፡ ባሪያዎቹም፡ ሕዝቡም፡ እንዲሁ፡ ይገባሉ። ፭ ነገር፡ ግን፡ ይህን፡ ቃል፡ ባትሰሙ፥ ይህ፡ ቤት፡ ወና፡ እን

ዲሆን ፡ በራሴ ፡ ምያለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፮ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ቤት ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— አንተ ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ገለዓድና ፡ እንደ ፡ ሊባኖስ ፡ ራስ ፡ ነህ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ በእርግጥ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ማንም ፡ የማይቀመጥባቸውም ፡ ከተሞች ፡ አደርግሃለሁ ። ፯ መሣሪያም ፡ የሚይዙትን ፡ አጥፊዎች ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ አዘጋጃለሁ ፥ የተመረጡትንም ፡ የዝግባ ፡ ዛፎችህን ፡ ይቈርጣሉ ፥ በእሳትም ፡ ውስጥ ፡ ይጥሉአቸዋል ። ፰ ብዙ ፡ አሕዛብም ፡ በዚህች ፡ ከተማ ፡ አጠገብ ፡ ያልፋሉ ፥ ሁሉም ፡ ባልንጀሮቻቸውን ፡— እግዚአብሔር ፡ በዚህች ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ፡ ለምን ፡ እንዲህ ፡ አደረገ ? ፱ ይላሉ ። እነርሱም ፡— የአምላካቸውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ትተው ፡ ለሌሎች ፡ አማልክት ፡ ስለ ፡ ሰገዱ ፡ ስላመለኩአቸውም ፡ ነዋ ፡ ብለው ፡ ይመልሳሉ ።

፲ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አይመለስምና ፥ የተወለደበትንም ፡ አገር ፡ አያይምና ፡ ለሚወጣ ፡ እጅግ ፡ አልቅሱ ፡ እንጂ ፡ ለሞተ ፡ አታልቅሱ ፡ አትዘኑለትም ። ፲፩ በአባቱ ፡ በኢዮስያስ ፡ ፋንታ ፡ ስለ ፡ ነገሠው ፡ ከዚህም ፡ ስፍራ ፡ ስለ ፡ ወጣው ፡ ስለ ፡ ይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ስለ ፡ ኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ ስለ ፡ ሰሎም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— ፲፪ እንግዲህም ፡ ወደዚህ ፡ አይመለስም ፥ በተማረከበት ፡ አገር ፡ ይሞታል ፡ እንጂ ፤ ይህችንም ፡ አገር ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አያይም ።

፲፫ ቤቱን ፡ በግፍ ፡ ሰገነቱንም ፡ በዓመፅ ፡ ለሚሠራ ፥ ባልንጀራውንም ፡ እንዲያው ፡ በከንቱ ፡ ፲፬ ለሚያሠራ ፥ ዋጋውንም ፡ ለማይሰጠው ፤ ለራሴ ፡ ሰፊ ፡ ቤት ፡ ትልቅም ፡ ሰገነት ፡ እሠራለሁ ፡ ለሚል ፥ መስኮትንም ፡ ለሚያወጣ ፥ በዝግባም ፡ ሥራ ፡ ለሚያስጌጥ ፥ በቀይ ፡ ቀለምም ፡ ለሚቀባው ፡ ፲፭ ወዮለት ! በዝግባ ፡ እንጨት ፡ ስለምትወዳደር ፡ በውኑ ፡ ትነግሣለህን ? በውኑ ፡ አባትህ ፡ አይበላምና ፡ አይጠጣም ፡ ነበርን ? ፍርድንና ፡ ጽድቅንስ ፡ አያደርግም ፡ ነበርን ? በዚያም ፡ ጊዜ ፡ መል ፲፮ ካም ፡ ሆኖለት ፡ ነበር ። የድሀውንና ፡ የችግረኛውን ፡ ፍርድ ፡ ይፈርድ ፡ ነበር ፥ በዚያም ፡ ጊዜ ፡ መልካም ፡ ሆኖ ፡ ነበር ። ይህ ፡ እኔን ፡ ማወቅ ፡ ፲፯ አይደለምን ? ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ዓይንህና ፡ ልብህ ፡ ግን ፡ ለስስት ፡ ንጹሕ ፡ ደምንም ፡ ለማፍሰስ ፡ ዓመፅንና ፡ ግፍንም ፡ ለመሥራት ፡ ብቻ ፡ ፲፰ ነው ። ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ስለ ፡ ኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ ስለ ፡ ኢዮአቄም ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ወንድሜ ፡ ሆይ ፥ ወዮ ! እያሉ ፡ አያለቅሱለትም ፥ ወይም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ፲፱ ወዮ ! እያሉ ፡ አያለቅሱለትም ። አህያም ፡ እንደሚቀበር ፡ ይቀበራል ፥ ከኢየሩሳሌምም ፡ በር ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ተጐትቶ ፡ ይጣላል ።

፳ ውሽሞችሽ ፡ ሁሉ ፡ ጠፍተዋልና ፡ ወደ ፡ ሊባኖስ ፡ ወጥተሽ ፡ ጩኺ ፤ በባሳን ፡ ላይ ፡ ድምፅሽን ፡ አንሺ ፤ በዓባሪምም ፡ ውስጥ ፡ ፳፩ ሆነሽ ፡ ጩኺ ። በደኅንነትሽ ፡ ጊዜ ፡ ተናገርሁሽ ፤ አንቺም ፡— አልሰማም ፡ አልሽ ። ከሕፃንነትሽ ፡ ጀምሮ ፡ ቃሌን ፡ አለመስማትሽ ፡ መንገድሽ ፡ ነው ። ፳፪ በግ ፡ ጠባቂዎችሽን ፡ ሁሉ ፡ ነፋስ ፡ ይጠብቃቸዋል ፥ ውሽሞችሽም ፡ ተማርከው ፡ ይሄዳሉ ፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ስለ ፡ ክፋትሽ ፡ ሁሉ ፡ ታፍሪያለሽ ፡ ትጐሳቈያለሽ ። ፳፫ አንቺ ፡ በሊባኖስ ፡ የምትቀመጪ ፥ በዝግባ ፡ ዛፍም ፡ ውስጥ ፡ ጎጆሽን ፡ የምትሠሪ ፡ ሆይ ፥ ምጥ ፡ እንደ ፡ ያዛት ፡ ሴት ፡ ሕማም ፡ በያዘሽ ፡ ጊዜ ፡ እንዴት ፡ ታጓሪያለሽ !

፳፬ እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ የኢዮአቄም ፡ ልጅ ፡ ኢኮንያን ፡ የቀኝ ፡ እጄ ፡ ማኅተም ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ እንኳ ፥ ከዚያ ፡ እነቅልህ ፡ ነበር ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ! ፳፭ ነፍስህንም ፡ ለሚሹት ፡ ለምትፈራቸውም ፡ እጅ ፥ ለባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ለናቡከደነፆር ፡ ለከለዳውያንም ፡ እጅ ፡ እሰጥሃለሁ ። ፳፮ አንተንም ፡ የወለደችህንም ፡ እናትህን ፡ ወዳልተወለዳችሁበት ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ አገር ፡ እጥላችኋለሁ ፥ በዚያም ፡ ትሞታላችሁ ። ፳፯ ይመለሱበትም ፡ ዘንድ ፡ ነፍሳቸው ፡ ወደምትመኛት ፡ ወደዚያች ፡ ምድር ፡ አይመለሱም ። ፳፰ በውኑ ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ ኢኮንያን ፡ የተናቀና ፡ የተሰበረ ፡ የሸክላ ፡ ዕቃ ፡ ነውን ? ወይስ ፡ እርሱ ፡ ለአንዳች ፡ የማይረባ ፡ የሸክላ ፡ ዕቃ ፡ ነውን ? እርሱና ፡ ዘሩስ ፡ በማያውቋት ፡ ምድር ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ተጥለው ፡ ወደቁ ? ፳፱ ምድር ፡ ሆይ ፥ ምድር ፡ ሆይ ፥ ምድር ፡ ሆይ ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስሚ ። ፴ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ከዚህ ፡ ሰው ፡ ዘር ፡ የሚከናወን ፡ በዳዊትም ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ የሚቀመጥ ፡ በይሁዳም ፡ የሚነግሥ ፡ እንግዲህ ፡ አይገኝምና ፡— መካን ፡ በዘመኑም ፡ የማይከናወንለት ፡ ሰው ፡ ብላችሁ ፡ጻፉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ የማሰማርያዬን ፡ በጎች ፡ ለሚያጠፉና ፡ ለሚበትኑ ፡ እረኞች ፡ ወዮላቸው ! ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፪ ስለዚህ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቤን ፡ ስለሚጠብቁ ፡ እረኞች ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በጎቼን ፡ በትናችኋል ፡ አባርራችኋቸውማል ፡ አልጐበኛችኋቸውምም ፤ እነሆ ፥ የሥራችሁን ፡ ክፋት ፡ እጐበኝባችኋለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፫ የመንጋዬም ፡ ቅሬታ ፡ ከበረርኋቸው ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ በረታቸው ፡ ሰብስቤ ፡ እመልሳቸዋለሁ ፤ እነርሱም ፡ ያፈራሉ ፡ ይበዙማል ። ፬ የሚጠብቋቸውን ፡ እረኞች ፡ አስነሣላቸዋለሁ ፥ ዳግመኛም ፡ አይፈሩምና ፡ አይደነግጡም ፥ ከእነርሱም ፡ አንድ ፡ አይጐድልም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፭ እነሆ ፥ ለዳዊት ፡ ጻድቅ ፡ ቍጥቋጥ ፡ የማስነሣበት ፡ ዘመን ፡ ይመጣል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፥ እርሱም ፡ እንደ ፡ ንጉሥ ፡ ይነግሣል ፥ ይከናወንለታልም ፥ በምድርም ፡ ፍርድንና ፡ ጽድቅን ፡ ያደርጋል ። ፮ በዘመኑም ፡ ይሁዳ ፡ ይድናል ፡ እስራኤልም ፡ ተዘልሎ ፡ ይቀመጣል ፥

የሚጠራበትም ፡ ስም ፡— እግዚአብሔር ፡ ጽድ
ቃችን ፡ ተብሎ ፡ ነው ።
፯ ስለዚህ ÷ እነሆ ፡— የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡
ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ያወጣ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔ
ርን ! ዳግመኛ ፡ የማይባልበት ፡ ዘመን ፡ ይመ
፰ ጣል ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ነገር ፡ ግን ፡—
የእስራኤልን ፡ ቤት ፡ ዘር ፡ ከሰሜን ፡ አገርና ፡ ካሰ
ደድኋቸውም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ያወጣና ፡ የመራ ፡
ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! ይባላል ፤ በምድራቸ
ውም ፡ ይቀመጣሉ ።
፱ ስለ ፡ ነቢያት ፤ ልቤ ፡ በውስጤ ፡ ተሰብሮአል ፡
አጥንቶቼም ፡ ሁሉ ፡ ታውከዋል ፤ ከእግዚአብ
ሔር ፡ የተነሣ ፡ ከቅዱስ ፡ ቃሉም ፡ የተነሣ ፡ የወ
ይን ፡ ጠጅ ፡ እንዳሸነፈው ፡ እንደ ፡ ሰከራም ፡
፲ ሰው ፡ ሆኛለሁ ። ምድር ፡ ከአመንዝሮች ፡ ተሞ
ልታለችና ÷ ከመርገምም ፡ የተነሣ ፡ ምድር ፡
አልቅሳለች ፤ የምድረ ፡ በዳ ፡ ማሰማርያ ፡ ደርቆ
አል ፤ አካሄዳቸው ፡ ክፉ ፡ ነው ÷ ብርታታቸ
፲፩ ውም ፡ ቅን ፡ አይደለም ። ነቢዩና ፡ ካህኑም ፡
ረክሰዋልና ÷ በቤቴም ፡ ውስጥ ፡ ክፋታቸውን ፡
፲፪ አግኝቻለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ስለዚህ ፡
መንገዳቸው ፡ በጨለማ ፡ እንዳለች ፡ እንደ ፡
ድጥ ፡ ስፍራ ፡ ትሆንባቸዋለች ÷ እነርሱም ፡
ፍግምግም ፡ ብለው ፡ ይወድቁባታል ፤ እኔም ፡
በምጐበኛቸው ፡ ዓመት ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ አመጣ
ባቸዋለሁና ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
፲፫ በሰማርያ ፡ ነቢያት ፡ ላይ ፡ ስንፍናን ፡ አይቻ
ለሁ ፤ በበአል ፡ ትንቢት ፡ ይናገሩ ፡ ነበር ÷ ሕዝ
፲፬ ቤንም ፡ እስራኤል ፡ ያስቱ ፡ ነበር ። በኢየሩሳ
ሌምም ፡ ነቢያት ፡ ላይ ፡ የሚያስደነግጥን ፡ ነገር ፡
አይቻለሁ ፤ ያመነዝራሉ ፡ በሐሰትም ፡ ይሄዳሉ ፤
ማንም ፡ ከክፋቱ ፡ እንዳይመለስ ፡ የክፉ ፡ አድ
ራጊዎችን ፡ እጅ ፡ ያበረታሉ ፤ ሁሉም ፡ እንደ ፡
ሰዶም ፡ የሚኖሩበትም ፡ እንደ ፡ ገሞራ ፡ ሆኑ
፲፭ ብኝ ። ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እነሆ ÷ ከኢየሩሳሌም ፡ ነቢያት ፡
ዘንድ ፡ ርኵሰት ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ወጥቶ
አልና ፡ እሬትን ፡ አበላቸዋለሁ ፡ የሐሞትንም ፡
ውኃ ፡ አጠጣቸዋለሁ ።
፲፮ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— ትንቢት ፡ የሚናገሩላችሁን ፡ የነቢያ
ትን ፡ ቃል ፡ አትስሙ ፤ ከንቱነትን ፡ ያስተምሩ
አችኋል ፤ ከእግዚአብሔር ፡ አፍ ፡ ሳይሆን ፡
ከገዛ ፡ ልባቸው ፡ የወጣውን ፡ ራእይ ፡ ይናገራሉ ።
፲፯ ለሚንቁኝ ፡ ሁልጊዜ ፡— እግዚአብሔር ፡—
ሰላም ፡ ይሆንላችኋል ፡ ብሎአል ፡ ይላሉ ፤
በልቡም ፡ እልከኝነት ፡ ለሚሄድ ፡ ሁሉ ፡— ክፉ ፡
፲፰ ነገር ፡ አያገኛችሁም ፡ ይላሉ ። ቃሉን ፡ ያዩና ፡
ይሰማ ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ምክር ፡
የቆመ ፡ ማን ፡ ነውና ? ቃሉንስ ፡ ያደመጠ ፡ የሰ
ማስ ፡ ማን ፡ ነው ?
፲፱ እነሆ ÷ የእግዚአብሔር ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ÷ እር
ሱም ፡ ቍጣው ÷ የሚያገለባብጥ ፡ ዐውሎ ፡
ነፋስ ፡ ወጥቶአል ፤ የዓመፀኞችን ፡ ራስ ፡ ይገለ
ባብጣል ። የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ የልቡን ፡ ፳
አሳብ ፡ ሠርቶ ፡ እስኪፈጽም ፡ ድረስ ፡ አይመ
ለስም ፤ በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ ፈጽማችሁ ፡ ታስ
ተውሉታላችሁ ። እኔ ፡ ሳልልካቸው ፡ እነዚህ ፡ ፳፩
ነቢያት ፡ ሮጡ ፤ እኔም ፡ ሳልነግራቸው ፡ ትንቢ
ትን ፡ ተናገሩ ። በምክሬ ፡ ግን ፡ ቢቆሙ ፡ ኖሮ ÷ ፳፪
ለሕዝቤ ፡ ቃሌን ፡ ባሰሙ ፡ ነበር ÷ ከክፉም ፡ መን
ገዳቸው ፡ ከሥራቸውም ፡ ክፋት ፡ በመለሱአ
ቸው ፡ ነበር ።
እኔ ፡ የቅርብ ፡ አምላክ ፡ ነኝ ፡ እንጂ ፡ የሩቅ ፡ ፳፫
አምላክ ፡ አይደለሁም ። ሰው ፡ በስውር ፡ ቢሸ ፳፬
ሽግ ÷ እኔ ፡ አላየውምን ? ሰማይንና ፡ ምድር
ንስ ፡ የሞላሁ ፡ እኔ ፡ አይደለሁምን ? ይላል ፡
እግዚአብሔር ። አለምሁ ፡ አለምሁ ፡ እያሉ ፡ ፳፭
በስሜ ፡ ሐሰትን ፡ የሚናገሩትን ፡ የነቢያትን ፡
ነገር ፡ ሰምቻለሁ ። ትንቢትን ፡ በሐሰት ፡ በሚ ፳፮
ናገሩ ÷ የልባቸውንም ፡ ሽንገላ ፡ በሚናገሩ ፡
በነቢያት ፡ ልብ ፡ ይህ ፡ የሚሆነው ፡ እስከ ፡
መቼ ፡ ነው ? አባቶቻቸው ፡ ስለ ፡ በአል ፡ ፳፯
ስሜን ፡ እንደ ፡ ረሱ ÷ እያንዳንዱ ፡ ለባልንጀ
ራው ፡ በሚናገራት ፡ ሕልማቸው ፡ ሕዝቤ ፡
ስሜን ፡ ለማስረሳት ፡ ያስባሉ ። የሚያልም ፡ ፳፰
ነቢይ ፡ ሕልምን ፡ ይናገር ፤ ቃሌም ፡ ያለበት ፡
ቃሌን ፡ በእውነት ፡ ይናገር ። ገለባ ፡ ከስንዴ ፡
ጋር ፡ ምን ፡ አለው ? በውኑ ፡ ቃሌ ፡ እንደ ፡ ፳፱
እሳት ÷ ድንጋዩንም ፡ እንደሚያደቅቅ ፡ መዶሻ ፡
አይደለችምን ? ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ስለ ፴
ዚህ ÷ እነሆ ÷ እያንዳንዱ ፡ ከባልንጀራው ፡
ዘንድ ፡ ቃሌን ፡ በሚሰርቁ ፡ ነቢያት ፡ ላይ ፡ ነኝ ÷
ይላል ፡ እግዚአብሔር ። እነሆ ÷ ከምላሳቸው ፡ ፴፩
ትንቢትን ፡ አውጥተው ፡— እርሱ ፡ ይላል ፡
በሚሉ ፡ ነቢያት ፡ ላይ ፡ ነኝ ÷ ይላል ፡ እግዚአ
ብሔር ። እነሆ ÷ ሐሰትን ፡ በሚያልሙ ፡ በሚ ፴፪
ናገሩም ፡ በሐሰታቸውና ፡ በድፍረታቸውም ፡
ሕዝቤን ፡ በሚያስቱ ፡ በነቢያት ፡ ላይ ፡ ነኝ ÷
ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ እኔም ፡ አልላክኋቸ
ውም ፡ አላዘዝኋቸውምም ፡ ለእነዚህም ፡ ሕዝብ ፡
በማናቸውም ፡ አይረቡአቸውም ÷ ይላል ፡ እግ
ዚአብሔር ።
ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ወይም ፡ ነቢይ ፡ ወይም ፡ ካህን ፡— ፴፫
የእግዚአብሔር ፡ ሸክም ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብሎ ፡
ቢጠይቅህ ÷ አንተ ፡— ሸክሙ ፡ እናንተ ፡ ናችሁ ÷
እጥላችሁማለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፡ ትላ
ቸዋለህ ። የእግዚአብሔር ፡ ሸክም ፡ የሚለ ፴፬
ውን ፡ ነቢይንና ፡ ካህንን ፡ ሕዝብንም ፡ ያን ፡
ሰውና ፡ ቤቱን ፡ እቀጣለሁ ። አንዱም ፡ አንዱ ፡ ፴፭
ለባልንጀራው ÷ አንዱም ፡ አንዱ ፡ ለወንድሙ ፡
እንዲህ ፡ ይበል ፡— እግዚአብሔር ፡ የመለሰው ፡
ምንድር ፡ ነው ? እግዚአብሔርስ ፡ ምን ፡ ነገር ፡
ተናገረ ? ለሰው ፡ ሁሉ ፡ ቃሉ ፡ ሸክም ፡ ይሆን ፴፮
በታልና ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሸክም ፡ ብላችሁ ፡
ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አትጥሩ ፤ የሠራዊትን ፡
ጌታ ፡ የአምላካችንን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የሕ
ያውን ፡ አምላክ ፡ ቃል ፡ ለውጣችኋልና ። ለነ ፴፯

ቢዩ ፡— እግዚአብሔር ፡ ምን ፡ መለሰልህ ? እግ
ዚአብሔርስ ፡ የተናገረው ፡ ምንድር ፡ ነው ?
፴፰፤ ትላለህ ፡ ነገር ፡ ግን ፡— የእግዚአብሔር ፡ ሸክም ፡
ብትሉ ፥ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
እኔ ፡— የእግዚአብሔር ፡ ሸክም ፡ አትበሉ ፡ ብዬ ፡
ልኬባችኋለሁና ፥ እናንተም ፡ ይህን ፡ ቃል ፡—
፴፱፤ የእግዚአብሔር ፡ ሸክም ፡ ብላችኋልና ፡ ስለዚህ ፥
እነሆ ፥ ፈጽሜ ፡ እረሳችኋለሁ ፡ እናንተንም ፡
ለእናንተና ፡ ለአባቶቻችሁም ፡ የሰጠኋትን ፡
፵፤ ከተማ ፡ ከፊቴ ፡ እጥላለሁ ። የዘላለምንም ፡
ስድብ ፡ ከቶም ፡ ተረስቶ ፡ የማይጠፋውን ፡ የዘ
ላለምን ፡ እፍረት ፡ አመጣባችኋለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩፤ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ የይሁዳን ፡
ንጉሥ ፡ የኢዮአቄምን ፡ ልጅ ፡ ኢኮንያንን ፡ የይ
ሁዳንም ፡ አለቆች ፡ ጠራቢዎችንና ፡ ብረት ፡ ሠራ
ተኞችን ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ማርኮ ፡ ወደ ፡ ባቢ
ሎን ፡ ካፈለሳቸው ፡ በኋላ ፥ እግዚአብሔር ፡ አሳ
የኝ ፥ እነሆም ፥ በእግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡
ፊት ፡ ሁለት ፡ ቅርጫት ፡ በለስ ፡ ተቀምጠው ፡
፪፤ ነበር ። በአንደኛይቱ ፡ ቅርጫት ፡ አስቀድሞ ፡
እንደ ፡ ደረሰ ፡ በለስ ፡ የሚመስል ፡ እጅግ ፡ መል
ካም ፡ በለስ ፡ ነበረባት ፤ በሁለተኛይቱ ፡ ቅርጫት ፡
ከክፋቱ ፡ የተነሣ ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ የማይቻል ፡
፫፤ እጅግ ፡ ክፉ ፡ በለስ ፡ ነበረባት ። እግዚአብሔ
ርም ፡— ኤርምያስ ፡ ሆይ ፥ የምታየው ፡ ምን
ድር ፡ ነው ? አለኝ ። እኔም ፡— በለስን ፡ አያለሁ ፤
እጅግ ፡ መልካም ፡ የሆነ ፡ መልካም ፡ በለስ ፥ ከክ
ፋቱም ፡ የተነሣ ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ የማይቻል ፡
እጅግ ፡ ክፉ ፡ የሆነ ፡ ክፉ ፡ በለስ ፡ ነው ፡ አልሁ ።
፬፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፭፤ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እንደዚህ ፡
እንደ ፡ መልካሙ ፡ በለስ ፥ እንዲሁ ፡ ከዚህ ፡
ስፍራ ፡ ወደ ፡ ከለዳውያን ፡ ምድር ፡ የሰደድሁ
ትን ፡ የይሁዳን ፡ ምርኮ ፡ ለበጎነት ፡ እመለከተ
፮፤ ዋለሁ ። ዓይኔንም ፡ ለበጎነት ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡
አደርጋለሁ ፡ ወደዚህችም ፡ ምድር ፡ እመልሳቸ
ዋለሁ ፤ እሠራቸዋለሁ ፡ እንጂ ፡ አላፈርሳቸ
ውም ፤ እተክላቸዋለሁ ፡ እንጂ ፡ አልነቅላቸ
፯፤ ውም ። እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡
የሚያውቅ ፡ ልብ ፡ እሰጣቸዋለሁ ፤ በፍጹምም ፡
ልባቸው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይመለሳሉና ፡ ሕዝብ ፡
ይሆኑኛል ፡ እኔም ፡ አምላክ ፡ እሆናቸዋለሁ ።
፰፤ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ከክ
ፋቱ ፡ የተነሣ ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ እንደማይቻል ፡
እንደ ፡ ክፉው ፡ በለስ ፥ እንዲሁ ፡ የይሁዳን ፡
ንጉሥ ፡ ሴዴቅያስን ፡ አለቆቹንም ፡ በዚህችም ፡
አገር ፡ የሚቀሩትን ፡ የኢየሩሳሌምን ፡ ቅሬታ ፡
በግብጽም ፡ አገር ፡ የሚቀመጡትን ፡ እጥላቸዋ
፱፤ ለሁ ። በማሳድዳቸውም ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ ለስ
ድብና ፡ ለምሳሌ ፡ ለማላገጫና ፡ ለእርግማን ፡
ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ በምድር ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡
ለመበተን ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣቸዋለሁ ። ለእነር ፲፤
ሱና ፡ ለአባቶቻቸውም ፡ ከሰጠኋቸው ፡ ምድር ፡
እስኪጠፉ ፡ ድረስ ፡ በመካከላቸው ፡ ሰይፍንና ፡
ራብን ፡ ቸነፈርንም ፡ እሰድዳለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ በኢ ፩፤
ዮአቄም ፡ በአራተኛው ፡ ዓመት ፥ በባቢሎን ፡
ንጉሥ ፡ በናቡከደነፆር ፡ በመጀመሪያው ፡
ዓመት ፥ ስለ ፡ ይሁዳ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡
ኤርምያስ ፡ የመጣው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። ይህ ፪፤
ንም ፡ ቃል ፡ ነቢዩ ፡ ኤርምያስ ፡ ለይሁዳ ፡ ሕዝብ ፡
ሁሉና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለተቀመጡ ፡ ሁሉ ፡
እንዲህ ፡ ሲል ፡ ተናገረው ፡— ከይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ፫፤
ከአሞጽ ፡ ልጅ ፡ ከኢዮስያስ ፡ ከአሥራ ፡ ሦስተ
ኛው ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡
ባሉት ፡ በእነዚህ ፡ በሀያ ፡ ሦስቱ ፡ ዓመታት ፥
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጣ ፥
እኔም ፡ ማልጄ ፡ ተነሥቼ ፡ ተናገርኋችሁ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ አልሰማችሁም ። እግዚአብሔርም ፡ ፬፤
ማልዶ ፡ ተነሥቶ ፡ ባሪያዎቹን ፡ ነቢያትን ፡ ወደ ፡
እናንተ ፡ ላከ ፤ እናንተም ፡ አላደመጣችሁም ፡
ጆሮአችሁንም ፡ አላዘነበላችሁም ። እርሱም ፡— ፭፤
ሁላችሁ ፡ እናንተ ፡ ከክፉ ፡ መንገዳችሁና ፡ ከሥ
ራችሁ ፡ ክፋት ፡ ተመለሱ ፤ እግዚአብሔርም ፡
ከዘላለም ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ለእናንተና ፡ ለአባቶ
ቻችሁ ፡ በሰጣችሁ ፡ ምድር ፡ ተቀመጡ ። ታመ ፮፤
ልኩአቸውም ፡ ትሰግዱላቸውም ፡ ዘንድ ፡ ሌሎ
ችን ፡ አማልክት ፡ አትከተሉ ፥ ክፉም ፡ እንዳላ
ደርግባችሁ ፡ በእጃችሁ ፡ ሥራ ፡ አታስቈጡኝ ፡
አለ ። ለእናንተ ፡ ጕዳት ፡ እንዲሆን ፡ በእጃችሁ ፡ ፯፤
ሥራ ፡ ታስቈጡኝ ፡ ዘንድ ፡ አልሰማችሁኝም ፥
ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ስለዚህ ፡ የሠራዊት ፡ ፰፤
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ቃሌን ፡
አልሰማችሁምና ፡ እነሆ ፥ ልኬ ፡ የሰሜንን ፡ ፱፤
ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ ባሪያዬንም ፡ የባቢሎንን ፡
ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆርን ፡ እወስዳለሁ ፥ በዚህ
ችም ፡ ምድር ፡ በሚቀመጡባትም ፡ ሰዎች ፡
በዙሪያዋም ፡ ባሉ ፡ በእነዚህ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ አመጣቸዋለሁ ፤ ፈጽሜም ፡ አጠፋቸዋ
ለሁ ፥ ለመደነቂያና ፡ ለማፍዋጫም ፡ ለዘላለ
ምም ፡ ባድማ ፡ አደርጋቸዋለሁ ። ከእነርሱም ፡ ፲፤
የእልልታን ፡ ድምፅና ፡ የደስታን ፡ ድምፅ ፥
የወንድ ፡ ሙሽራን ፡ ድምፅና ፡ የሴት ፡ ሙሽራን ፡
ድምፅ ፥ የወፍጮንም ፡ ድምፅ ፡ የመብራት
ንም ፡ ብርሃን ፡ አስቀራለሁ ። ይህችም ፡ ምድር ፡ ፲፩፤
ሁሉ ፡ ባድማና ፡ መደነቂያ ፡ ትሆናለች ፤ እነዚ
ህም ፡ አሕዛብ ፡ ለባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ሰባ ፡ ዓመት ፡
ይገዛሉ ።
ሰባው ፡ ዓመትም ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፥ የባቢ ፲፪፤
ሎንን ፡ ንጉሥና ፡ ያንን ፡ ሕዝብ ፡ ስለ ፡ ኃጢአ
ታቸው ፡ እቀጣለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፥
የከለዳውያንንም ፡ ምድር ፡ ለዘላለም ፡ ባድማ ፡
አደርጋታለሁ ። በእርስዋም ፡ ላይ ፡ የተናገር ፲፫፤

ሁትን ፡ ቃሌን ፡ ሁሉ ፥ ማለት ፡ ኤርምያስ ፡
በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ትንቢት ፡ የተናገረውን ፡
በዚህች ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈውን ፡ ሁሉ ፥ በዚ
፲፬ ያች ፡ ምድር ፡ አመጣለሁ ። ብዙ ፡ አሕዛብና ፡
ታላላቆች ፡ ነገሥታት ፡ እነርሱን ፡ ያስገዙአቸ
ዋል ፤ እኔም ፡ እንደ ፡ አደራረጋቸውና ፡ እንደ ፡
እጃቸው ፡ ሥራ ፡ እከፍላቸዋለሁ ።

፲፭ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይለኛል ፡— የዚህን ፡ ቍጣ ፡ የወይን ፡
ጠጅ ፡ ጽዋ ፡ ከእጄ ፡ ውሰድ ፡ አንተንም ፡ የምሰ
ድድባቸውን ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ አጠጣቸው ።
፲፮ ከምሰድድባቸውም ፡ ሰይፍ ፡ የተነሣ ፡ ይጠጣሉ ፡
፲፯ ይወላገዱማል ፡ ያብዳሉም ። ከእግዚአብሔ
ርም ፡ እጅ ፡ ጽዋውን ፡ ወሰድሁ ፥ እግዚአብሔ
ርም ፡ እኔን ፡ የሰደደባቸውን ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡
፲፰ አጠጣኋቸው ። ዛሬ ፡ እንደ ፡ ሆነው ፡ ሁሉ ፡
በድማና ፡ መደነቂያ ፡ ማፍዋጫም ፡ እርግማ
ንም ፡ አደርጋቸው ፡ ዘንድ ፡ ኢየሩሳሌምንና ፡
የይሁዳን ፡ ከተሞች ፡ ነገሥታትዋንም ፡ አለቆ
፲፱ ችዋንም ፡ አጠጣኋቸው ። የግብጽንም ፡ ንጉሥ ፡
ፈርዖንን ፡ ባሪያዎቹንም ፡ አለቆቹንም ፡ ሕዝቡ
፳ ንም ፡ ሁሉ ፥ የተደበለቀውንም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፥
የዖፅ ፡ ምድር ፡ ነገሥታትንም ፡ ሁሉ ፥ የፍልስ
ጥኤም ፡ ምድር ፡ ነገሥታትንም ፡ ሁሉ ፡ አስቀሎ
ናንም ፡ ጋዛንም ፡ አቃሮንንም ፡ የአዛጦንንም ፡
፳፩ ቅሬታ ፥ ኤዶምያስንም ፥ ሞዓብንም ፥ የአሞን
፳፪ ንም ፡ ልጆች ፥ የጢሮስን ፡ ነገሥታትም ፡ ሁሉ ፥
የሲዶናን ፡ ነገሥታትም ፡ ሁሉ ፥ በባሕር ፡ ማዶ ፡
፳፫ ያለች ፡ የደሴት ፡ ነገሥታትንም ፥ ድዳንንም ፥
ቴማንንም ፥ ቡዝንም ፥ ጠጕራቸውንም ፡ የሚ
፳፬ ቈርጡትን ፡ ሁሉ ፥ የዓረብ ፡ ነገሥታትንም ፡
ሁሉ ፥ በምድረ ፡ በዳ ፡ የሚቀመጡ ፡ የድብ
፳፭ ልቅ ፡ ሕዝብ ፡ ነገሥታትንም ፡ ሁሉ ፥ የዘምሪ ፡
ነገሥታትንም ፡ ሁሉ ፥ የኤላም ፡ ነገሥታትንም ፡
፳፮ ሁሉ ፥ የሜዶን ፡ ነገሥታትንም ፡ ሁሉ ፥ የቀረ
ቡና ፡ የራቁ ፥ አንዱ ፡ ከሌላው ፡ ጋር ፡ ያሉ ፡
የሰሜን ፡ ነገሥታትንም ፡ ሁሉ ፥ በምድር ፡ ፊት ፡
ላይ ፡ ያሉ ፡ የዓለም ፡ መንግሥታትንም ፡ ሁሉ ፡
አጠጣኋቸው ፤ የሼሻክም ፡ ንጉሥ ፡ ከእነርሱ ፡
በኋላ ፡ ይጠጣል ።

፳፯ አንተም ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራ
ዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
በመካከላችሁ ፡ ከምሰድደው ፡ ሰይፍ ፡ የተነሣ ፡
ጠጡ ፥ ስከሩም ፥ አስታውኩም ፡ ውደቁም ፥
ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ አትነሡም ፡ በላቸው ።
፳፰ ይጠጡም ፡ ዘንድ ፡ ጽዋውን ፡ ከእጅህ ፡ ለመቀ
በል ፡ እንቢ ፡ ቢሉ ፡— የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ፈጽማችሁ ፡ ትጠ
፳፱ ጣላችሁ ፡ በላቸው ። እነሆ ፥ ስሜ ፡ የተጠራብ
ትን ፡ ከተማ ፡ አስጨንቃት ፡ ዘንድ ፡ እጀምራ
ለሁ ፤ በውኑ ፡ እናንተ ፡ ያልተቀጣችሁ ፡ ትሆናላ
ችሁን ? በምድር ፡ በሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሰይ
ፍን ፡ እጠራለሁና ፡ ያለ ፡ ቅጣት ፡ አትቀሩም ፥
ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፴ ስለዚህም ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ትንቢት ፡
ትናገርባቸዋለህ ፥ እንዲህም ፡ ትላቸዋለህ ፡—
እግዚአብሔር ፡ በላይ ፡ ሆኖ ፡ ይጮኻል ፥ በቅ
ዱስ ፡ ማደሪያውም ፡ ሆኖ ፡ ድምፁን ፡ ያሰማል ፤
በበረቱ ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡ ይጮኻል ፥ ወይንም ፡
እንደሚጠምቁ ፡ በምድር ፡ በሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡
፴፩ ላይ ፡ ይጮኻል ። እግዚአብሔር ፡ ከአሕዛብ ፡
ጋር ፡ ክርክር ፡ አለውና ፡ ድምፅ ፡ እስከ ፡ ምድር ፡
ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ይደርሳል ፤ ከሥጋ ፡ ለባሽ ፡
ሁሉ ፡ ጋር ፡ ይፋረዳል ፥ ኃጢአተኞችንም ፡
ለሰይፍ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣል ፥ ይላል ፡ እግዚአብ
ሔር ።

፴፪ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እነሆ ፥ ክፉ ፡ ነገር ፡ ከሕዝብ ፡ ወደ ፡
ሕዝብ ፡ ይወጣል ፥ ጽኑም ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡
፴፫ ከምድር ፡ ዳርቻ ፡ ይነሣል ። በዚያም ፡ ቀን ፡
የእግዚአብሔር ፡ ግዳዮች ፡ ከምድር ፡ ዳር ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳር ፡ ድረስ ፡ ይሆናሉ ፤
አይለቀስላቸውም ፤ በምድር ፡ ላይ ፡ እንደ ፡
ጕድፍ ፡ ይሆናሉ ፡ እንጂ ፡ አይከማቹም ፡ አይ
፴፬ ቀበሩምም ። ትታረዱና ፡ ትበተኑ ፡ ዘንድ ፡ ቀና
ችሁ ፡ ደርሶአልና ፥ እንደ ፡ ተወደደም ፡ የሸክላ ፡
ዕቃ ፡ ትወድቃላችሁና ፡ እናንተ ፡ እረኞች ፥
አልቅሱ ፡ ጩኹም ፤ እናንተ ፡ የመንጋ ፡ አው
፴፭ ራዎች ፥ በአመድ ፡ ውስጥ ፡ ተንከባለሉ ። ሽሽ
ትም ፡ ከእረኞች ፡ ማምለጥም ፡ ከመንጋ ፡ አው
፴፮ ራዎች ፡ ይጠፋል ። እግዚአብሔር ፡ ማሰማር
ያቸውን ፡ አጥፍቶአልና ፡ የእረኞች ፡ ጩኸት ፡
ድምፅ ፡ የመንጋ ፡ አውራዎችም ፡ ልቅሶ ፡
፴፯ ሆኖአል ። ከእግዚአብሔር ፡ ጽኑ ፡ ቍጣ ፡ የተ
፴፰ ነሣ ፡ የሰላም ፡ በረት ፡ ፈርሶአል ። እንደ ፡ አን
በሳ ፡ መደቡን ፡ ለቅቆአል ፤ ከአስጨናቂውም ፡
ሰይፍና ፡ ከጽኑ ፡ ቍጣው ፡ የተነሣ ፡ ምድራ
ቸው ፡ ባድማ ፡ ሆናለችና ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ በኢዮ
አቄም ፡ መንግሥት ፡ መጀመሪያ ፡ ይህ ፡ ቃል ፡
፪ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ መጣ ። እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በእግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ አደባባይ ፡ ቁም ፥ በእግዚአብሔርም ፡
ቤት ፡ ውስጥ ፡ ይሰግዱ ፡ ዘንድ ፡ ለሚመጡት ፡
ለይሁዳ ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ትነግራቸው ፡ ዘንድ ፡
ያዘዝሁህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ተናገራቸው ፤ አንዲ
፫ ትም ፡ ቃል ፡ አታጕድል ። ምናልባት ፡ ይሰሙ ፥
ከክፉ ፡ መንገዳቸውም ፡ ይመለሱ ፡ ይሆናል ፤
እኔም ፡ ስለ ፡ ሥራቸው ፡ ክፋት ፡ ያሰብሁባቸ
፬ ውን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እተዋለሁ ። እንዲህም ፡ በላ
ቸው ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
በፊታችሁ ፡ በሰጠኋት ፡ ሕጌ ፡ ትሄዱ ፡ ዘንድ ፡
፭ ባትሰሙኝ ፥ ያልሰማችሁትን ፡ በማለዳ ፡ ተነ
ሥቼ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ የላክኋቸውን ፡ የባሪያዎ
፮ ቼን ፡ የነቢያትን ፡ ቃል ፡ ባትሰሙ ፥ ይህን ፡ ቤት ፡
እንደ ፡ ሴሎ ፡ አደርገዋለሁ ፥ ይህችንም ፡ ከተማ ፡

ለምድር ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ እርግማን ፡ አደርጋ
ታለሁ ።

፯ ካህናቱም ፡ ነቢያቱም ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ኤር
ምያስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ይህን ፡ ቃል ፡
፰ ሲናገር ፡ ሰሙ ። ኤርምያስም ፡ ለሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡
ይናገር ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያዘዘውን ፡
ነገር ፡ ሁሉ ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ ካህናትና ፡ ነቢ
ያት ፡ ሕዝብም ፡ ሁሉ ፡— ሞትን ፡ ትሞታለህ ።
፱ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡— ይህ ፡ ቤት ፡ እንደ ፡
ሴሎ ፡ ይሆናል ፥ ይህችም ፡ ከተማ ፡ በድማና ፡
ወና ፡ ትሆናለች ፡ ብለህ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትንቢት ፡
ተናገርህ ? ብለው ፡ ያዙት ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ በኤርምያስ ፡
ላይ ፡ ተሰብስበው ፡ ነበር ።

፲ የይሁዳም ፡ አለቆች ፡ ይህን ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡
ከንጉሥ ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
ወጡ ፥ በአዲሱም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
፲፩ ደጅ ፡ መግቢያ ፡ ተቀመጡ ። ካህናቱና ፡ ነቢያ
ቱም ፡ ለአለቆቹና ፡ ለሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡— በጆሮ
አችሁ ፡ እንደ ፡ ሰማችሁ ፡ በዚህች ፡ ከተማ ፡
ላይ ፡ ትንቢት ፡ ተናግሮአልና ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ ሞት ፡
፲፪ የሚገባው ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ተናገሩ ። ኤርምያ
ስም ፡ ለአለቆችና ፡ ለሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡
ብሎ ፡ ተናገረ ፡— በሰማችሁት ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡
በዚህች ፡ ቤትና ፡ በዚህች ፡ ከተማ ፡ ላይ ፡ ትን
ቢት ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልኮኛል ።
፲፫ አሁንም ፡ መንገዳችሁንና ፡ ሥራችሁን ፡ አሳ
ምሩ ፥ የአምላካችሁንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ቃል ፡ ስሙ ፤ እግዚአብሔርም ፡ የተናገረባች
፲፬ ሁን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ይተዋል ። እኔ ፡ ግን ፥
እነሆ ፥ በእጃችሁ ፡ ነኝ ፤ በዓይናችሁ ፡ መልካ
፲፭ ምና ፡ ቅን ፡ የመሰለውን ፡ አድርጉብኝ ። ነገር ፡
ግን ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ በጆሮአችሁ ፡ እና
ገር ፡ ዘንድ ፡ በእውነት ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡
እናንተ ፡ ልኮኛልና ፡ ብትገድሉኝ ፡ ንጹሕ ፡
ደምን ፡ በራሳችሁና ፡ በዚህች ፡ ከተማ ፡ በሚኖሩ
ባትም ፡ ላይ ፡ እንድታመጡ ፡ በእርግጥ ፡ እወቁ ።

፲፮ አለቆቹና ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ለካህናትና ፡ ለነ
ቢያት ፡— ይህ ፡ ሰው ፡ በአምላካችን ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ ስም ፡ ተናግሮናልና ፡ ሞት ፡ አይገባ
፲፯ ውም ፡ አሉ ። ከአገሩ ፡ ሽማግሌዎችም ፡ ሰዎች ፡
ተነሥተው ፡ ለሕዝቡ ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡
፲፰ ብለው ፡ ተናገሩ ። ሞሬታዊው ፡ ሚክያስ ፡ በይ
ሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በሕዝቅያስ ፡ ዘመን ፡ ነቢይ ፡ ነበረ ፤
ለይሁዳም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡— የሠራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ጽዮን ፡
እንደ ፡ እርሻ ፡ ትታረሳለች ፥ ኢየሩሳሌምም ፡
የፍርስራሽ ፡ ክምር ፡ ትሆናለች ፥ የቤቱም ፡
ተራራ ፡ እንደ ፡ ዱር ፡ ከፍታ ፡ ይሆናል ፡ ብሎ ፡
፲፱ ተናገረ ። በውኑ ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ሕዝቅያ
ስና ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ገደሉትን ? በውኑ ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ አልፈሩምን ? ወደ ፡ እግዚአብ
ሔርስ ፡ አልተማለሉምን ? እግዚአብሔርስ ፡
የተናገረባቸውን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አይተውምን ?
እኛም ፡ በነፍሳችን ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ክፋት ፡ እና
ደርጋለን ።

፳ ደግሞም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ትንቢት ፡
የተናገረ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ እርሱም ፡ የቂ
ርያትይዓሪም ፡ ሰው ፡ የሸማያ ፡ ልጅ ፡ ኦርዮ ፡
ይባል ፡ ነበር ፤ በዚህችም ፡ ከተማ ፡ በዚህችም ፡
ምድር ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ኤርምያስ ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡
፳፩ ትንቢት ፡ ተናገረ ። ንጉሡም ፡ ኢዮአቄም ፡
ኃያላኑም ፡ ሁሉ ፡ አለቆቹም ፡ ሁሉ ፡ ቃሉን ፡
በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሡ ፡ ሊገድለው ፡ ፈለገ ፤ ኦር
ዮም ፡ ይህን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ፈርቶ ፡ ሸሸ ፡ ወደ ፡
፳፪ ግብጽም ፡ ገባ ። ንጉሡም ፡ ኢዮአቄም ፡ የዓ
ክቦርን ፡ ልጅ ፡ ኤልናታንን ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡
፳፫ ሌሎችን ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ላካቸው ፤ ከግ
ብጽም ፡ ኦርዮን ፡ አውጥተው ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡
ወደ ፡ ኢዮአቄም ፡ ይዘውት ፡ መጡ ፤ እርሱም ፡
በሰይፍ ፡ ገደለው ፡ ሬሳውንም ፡ ከቡራን ፡ በል
፳፬ ሆኑ ፡ ሰዎች ፡ መቃብር ፡ ጣለው ። ነገር ፡ ግን ፡
በሕዝቡ ፡ እጅ ፡ እንዳይሰጥና ፡ እንዳይገድሉት ፡
የሳፋን ፡ ልጅ ፡ የአኪቃም ፡ እጅ ፡ ከኤርምያስ ፡
ጋር ፡ ነበረች ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

፩ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ በኢዮአ
ቄም ፡ መንግሥት ፡ መጀመሪያ ፡ ይህ ፡ ቃል ፡ ከእ
ግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ መጣ ።
፪ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይለኛል ፡— እስራትና ፡
ቀንበር ፡ ሥራ ፡ በአንገትህም ፡ ላይ ፡ አድርግ ፤
፫ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ንጉሥም ፡ ወደ ፡ ሴዴቅያስ ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ በመጡት ፡ መልእክተኞች ፡ እጅ ፡
ወደ ፡ ኤዶምያስ ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ሞዓብም ፡
ንጉሥ ፡ ወደ ፡ አሞንም ፡ ልጆች ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡
ጢሮስም ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ሲዶናም ፡ ንጉሥ ፡
፬ ላካቸው ። ለጌቶቻቸውም ፡ እንዲነግሩ ፡ እን
ዲህ ፡ ብለህ ፡ እዘዛቸው ፡— የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፡— ለጌቶቻችሁ ፡ እንዲህ ፡ በሉ ፡—
፭ ምድሪቱን ፡ በምድርም ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ ያሉትን ፡
ሰዎችንና ፡ እንስሶችን ፡ በታላቅ ፡ ኃይሌና ፡ በተ
ዘረጋችው ፡ ክንዴ ፡ ፈጥሬአለሁ ፤ ለዓይኔም ፡
፮ መልካም ፡ ለሆነው ፡ እሰጣታለሁ ። አሁንም ፡
እነዚህን ፡ ምድሮች ፡ ሁሉ ፡ ለባሪያዬ ፡ ለባቢ
ሎን ፡ ንጉሥ ፡ ለናቡከደነፆር ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡
ሰጥቻለሁ ፤ ይገዙለትም ፡ ዘንድ ፡ የምድረ ፡ በዳ ፡
፯ አራዊትን ፡ ደግሞ ፡ ሰጥቼዋለሁ ። የገዛ ፡ ራሱም ፡
ምድር ፡ ጊዜ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ አሕዛብ ፡
ሁሉ ፡ ለእርሱና ፡ ለልጁ ፡ ለልጅ ፡ ልጁም ፡ ይገ
ዛሉ ፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ብዙ ፡ አሕዛብና ፡ ታላ
፰ ላቆች ፡ ነገሥታት ፡ እርሱን ፡ ያስገዙታል ። ለባ
ቢሎን ፡ ንጉሥም ፡ ለናቡከደነፆር ፡ የማይገዛ
ውን ፥ ከባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ቀንበር ፡ በታች ፡
አንገቱን ፡ ዝቅ ፡ የማያደርገውን ፡ ሕዝብና ፡ መን
ግሥት ፥ ያን ፡ ሕዝብ ፡ በእጁ ፡ እስካጠፋው ፡
ድረስ ፡ በሰይፍና ፡ በራብ ፡ በቸነፈርም ፡ እቀጣ

ለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፱ እናንተ ፡ ግን ፡— ለባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ አትገዙም ፡ የሚሉአችሁን ፡ ነቢያቶቻችሁንና ፡ ምዋርተኞቻችሁን ÷ ሕልም ፡ አላሚዎቻችሁንና ፡ ቃላተኞቻችሁን ፡ መተተኞቻችሁንም ፡ አትስሙ ፤ ፲ ከምድራችሁ ፡ እንዳያርቁአችሁ ÷ እኔም ፡ እንዳሳድዳችሁ ፡ እናንተም ፡ እንድትጠፉ ፡ ሐሰተኛ ፡ ትንቢትን ፡ ይናገሩላችኋልና ። ፲፩ ነገር ፡ ግን ፡ ከባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ቀንበር ፡ በታች ፡ አንገቱን ፡ ዝቅ ፡ የሚያደርገውንና ፡ የሚገዛለትን ፡ ሕዝብ ፡ በአገሩ ፡ ላይ ፡ እተወዋለሁ ፤ እነርሱም ፡ ያርሱአታል ፡ ይቀመጡባትማል ።

፲፪ ለይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ለሴዴቅያስም ፡ በዚህ ፡ ቃል ፡ ተናገርሁ ፡— ከባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ቀንበር ፡ በታች ፡ አንገታችሁን ፡ ዝቅ ፡ አድርጉ ፡ ለእርሱና ፡ ለሕዝቡም ፡ ተገዙላቸው ፡ በሕይወትም ፡ ኑሩ ። ፲፫ ለባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ይገዛ ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ ስላለ ፡ ሕዝብ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተናገረ ÷ አንተና ፡ ሕዝብህ ፡ በሰይፍና ፡ በራብ ፡ በቸነፈርም ፡ ለምን ፡ ትሞታላችሁ ? ፲፬ ሐሰተኛን ፡ ትንቢት ፡ ይናገሩላችኋልና ፡— ለባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ አትገዙም ፡ የሚሉአችሁን ፡ የነቢያትን ፡ ቃል ፡ አትስሙ ። ፲፭ እኔ ፡ አልላክኋቸውምና ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እኔ ፡ እንዳሳድዳችሁ ÷ እናንተና ፡ ትንቢት ፡ የሚናገሩላችሁ ፡ ነቢያትም ፡ እንድትጠፉ ፡ በስሜ ፡ ሐሰተኛ ፡ ትንቢትን ፡ ይናገራሉ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፲፮ ለካህናትም ፡ ለዚህም ፡ ሕዝብ ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ ተናገርሁ ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ሐሰተኛውን ፡ ትንቢት ፡ ይናገሩላችኋልና ፡— የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ዕቃ ፡ በቅርብ ፡ ጊዜ ፡ ከባቢሎን ፡ ይመለሳል ፡ የሚሉአችሁን ፡ የነቢያቶቻችሁን ፡ ቃል ፡ አትስሙ ። ፲፯ እነርሱም ፡ አትስሙ ፤ ለባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ተገዙ ፡ በሕይወትም ፡ ኑሩ ። ይህችስ ፡ ከተማ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ በድማ ፡ ትሆናለች ? ፲፰ እነርሱ ፡ ግን ፡ ነቢያት ፡ ቢሆኑ ÷ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ቢገኝ ÷ በእግዚአብሔር ፡ ቤትና ፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ቤት ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ የቀረችው ፡ ዕቃ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ እንዳትሄድ ፡ ወደ ፡ ሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይማለሉ። ፲፱ ፳ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ የይሁዳን ፡ ንጉሥ ፡ የኢዮአቄምን ፡ ልጅ ፡ ኢኮንያንንና ፡ የይሁዳንና ፡ የኢየሩሳሌምን ፡ ከበርቴዎች ፡ ሁሉ ፡ ማርኮ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ በፈለሳቸው ፡ ጊዜ ፡ ስላልወሰዳቸው ፡ ዓምዶች ፡ ስለ ፡ ኵሬውም ፡ ስለ ፡ መቀመጫዎቹም ፡ በዚህችም ፡ ከተማ ፡ ስለ ፡ ቀረች ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ የሠራዊት ፡ ፳፩ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፤ በእግዚአብሔር ፡ ቤትና ፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ቤት ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ ስለ ፡ ቀረችው ፡ ዕቃ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ ፳፪ ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ትወሰዳለች ፡ እስከምጐበኛትም ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ ትኖራለች ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ አወጣታለሁ ፡ ወደዚህም ፡ ስፍራ ፡ እመልሳታለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

፩ በዚያም ፡ ዓመት ÷ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በሴዴቅያስ ፡ መንግሥት ፡ መጀመሪያ ÷ በአራተኛው ፡ ዓመት ፡ በአምስተኛው ፡ ወር ፡ ነቢዩ ፡ የገባዖን ፡ ሰው ፡ የዓዙር ፡ ልጅ ፡ ሐናንያ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በካህናትና ፡ በሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ፪ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረኝ ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ይናገራል ፡— የባቢሎንን ፡ ንጉሥ ፡ ቀንበር ፡ ሰብሬአለሁ ። ፫ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ከዚህች ፡ ስፍራ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ የወሰዳትን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ በሁለት ፡ ዓመት ፡ ውስጥ ፡ ወደዚህች ፡ ስፍራ ፡ እመልሳታለሁ ፤ ፬ ወደ ፡ ባቢሎንም ፡ የሄዱትን ፡ የይሁዳን ፡ ንጉሥ ፡ የኢዮአቄምን ፡ ልጅ ፡ ኢኮንያንንና ፡ የይሁዳን ፡ ምርኮ ፡ ሁሉ ፡ ወደዚህች ፡ ስፍራ ፡ እመልሳቸዋለሁ ፤ የባቢሎንን ፡ ንጉሥ ፡ ቀንበር ፡ እሰብራለሁና ።

፭ ነቢዩ ፡ ኤርምያስም ፡ በካህናቱና ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በቆሙት ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ለነቢዩ ፡ ለሐናንያ ፡ ተናገረ ። ፮ ነቢዩም ፡ ኤርምያስ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— አሜን ÷ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ያድርግ ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ዕቃ ፡ ምርኮውንም ፡ ሁሉ ፡ ከባቢሎን ፡ ወደዚህ ፡ ስፍራ ፡ በመመለስ ፡ እግዚአብሔር ፡ የተናገርኸውን ፡ ትንቢት ፡ ይፈጽም ። ፯ ነገር ፡ ግን ፡ በጆሮህና ፡ በሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ጆሮ ፡ የምናገረውን ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ስማ ፤ ፰ ከጥንት ፡ ከእኔና ፡ ከአንተ ፡ በፊት ፡ የነበሩ ፡ ነቢያት ፡ በብዙ ፡ አገርና ፡ በታላላቅ ፡ መንግሥታት ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ሰልፍና ፡ ስለ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ስለ ፡ ቸነፈርም ፡ ትንቢት ፡ ተናገሩ ። ፱ ስለ ፡ ሰላም ፡ የተናገረ ፡ ነቢይ ÷ የነቢዩ ፡ ቃል ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ÷ እግዚአብሔር ፡ በእውነት ፡ የሰደደው ፡ ነቢይ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይታወቃል ።

፲ ነቢዩም ፡ ሐናንያ ፡ ቀንበሩን ፡ ከነቢዩ ፡ ከኤርምያስ ፡ አንገት ፡ ወስዶ ፡ ሰበረው ። ፲፩ ሐናንያም ፡ በሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እንዲሁ ፡ በሁለት ፡ ዓመት ፡ ውስጥ ፡ የባቢሎንን ፡ ንጉሥ ፡ የናቡከደነፆርን ፡ ቀንበር ፡ ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ አንገት ፡ እሰብራለሁ ፡ አለ ። ነቢዩም ፡ ኤርምያስ ፡ መንገዱን ፡ ሄደ ።

፲፪ ነቢዩም ፡ ሐናንያ ፡ ቀንበሩን ፡ ከነቢዩ ፡ ከኤርምያስ ፡ አንገት ፡ ከሰበረ ፡ በኋላ ÷ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ፲፫ ሂድ ÷ ለሐናንያ ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡ ንገረው ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— አንተ ፡ የእንጨትን ፡ ቀንበር ፡ ሰብረሃል ÷ እኔ ፡ ግን ፡ በእርሱ ፡ ፋንታ ፡ የብረትን ፡ ቀንበር ፡ እሠራለሁ ። ፲፬ የእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡

ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— ለባቢ
ሎን ፡ ንጉሥ ፡ ለናቡከደነፆር ፡ ይገዙለት ፡ ዘንድ ፡
የብረትን ፡ ቀንበር ፡ በእነዚህ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡
አንገት ፡ ላይ ፡ አድርጌአለሁ ፤ እነርሱም ፡ ይገ
ዙለታል ፥ የምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊትን ፡ ደግሞ ፡
፲፭ ሰጥቼዋለሁ ። ነቢዩም ፡ ኤርምያስ ፡ ነቢዩን ፡
ሐናንያን ፡— ሐናንያ ፡ ሆይ ፥ ስማ ፤ ይህ ፡
ሕዝብ ፡ በሐሰት ፡ እንዲታመን ፡ አድርገሃል ፡
፲፮ እንጂ ፡ እግዚአብሔር ፡ አልላከህም ። ስለዚህ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ፥ ከም
ድር ፡ ላይ ፡ እሰድድሃለሁ ፤ በእግዚአብሔር ፡
ላይ ፡ ዓመፅን ፡ ተናግረሃልና ፡ በዚህ ፡ ዓመት ፡
፲፯ ትሞታለህ ፡ አለው ። ነቢዩም ፡ ሐናንያ ፡ በዚ
ያው ፡ ዓመት ፡ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ሞተ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

፩ ነቢዩ ፡ ኤርምያስ ፡ ወደ ፡ ተረፉት ፡ የምርኮ ፡
ሽማግሌዎች ፥ ወደ ፡ ካህናቱም ፥ ወደ ፡ ነቢያ
ቱም ፥ ናቡከደነፆር ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ባቢ
ሎን ፡ ማርኮ ፡ ወዳፈለሰውም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡
ከኢየሩሳሌም ፡ የላከው ፡ የደብዳቤው ፡ ቃል ፡
፪ ይህ ፡ ነው ። ይህም ፡ የሆነው ፡ ንጉሡ ፡ ኢኮ
ንያን ፡ እናቱም ፡ እቴጌይቱ ፡ ጃንደረቦቹም ፡
የይሁዳና ፡ የኢየሩሳሌምም ፡ አለቆች ፡ ጠራቢ
ዎችና ፡ ብረት ፡ ሠራተኞችም ፡ ከኢየሩሳሌም ፡
፫ ከወጡ ፡ በኋላ ፡ ነው ። ኤርምያስ ፡ የይሁዳ ፡
ንጉሥ ፡ ሴዴቅያስ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡
ወደ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ በላካቸው ፡
በሳፋን ፡ ልጅ ፡ በኤልዓሣና ፡ በኬልቅያስ ፡
ልጅ ፡ በገማርያ ፡ እጅ ፡ ደብዳቤውን ፡ እንዲህ ፡
፬ ሲል ፡ ላከው ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠ
ራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከኢየሩሳሌም ፡
ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ላስማረከኋቸው ፡ ምርኮኞች ፡
፭ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ቤት ፡ ሠርታችሁ ፡
ተቀመጡ ፥ አታክልትም ፡ ተክላችሁ ፡ ፍሬ
፮ ዋን ፡ ብሉ ፤ ተጋቡ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡
ልጆችንም ፡ ውለዱ ፤ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆ
ቻችሁንም ፡ አጋቡ ፥ እነርሱም ፡ ወንዶችንና ፡
ሴቶችን ፡ ልጆች ፡ ይውለዱ ፤ ከዚያም ፡ ተባዙ ፡
፯ ጥቂቶችም ፡ አትሁኑ ። በእርስዋ ፡ ሰላም ፡ ሰላም ፡
ይሆንላችኋልና ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ላስማረክኋችሁ ፡
ከተማ ፡ ሰላምን ፡ ፈልጉ ፥ ስለ ፡ እርስዋም ፡ ወደ ፡
፰ እግዚአብሔር ፡ ጸልዩ ። የእስራኤልም ፡ አም
ላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላልና ፡— በመካከላችሁ ፡ ያሉት ፡ ነቢያቶቻች
ሁና ፡ ምዋርተኞቻችሁ ፡ አያታልሉአችሁ ፥
እናንተም ፡ የምታልሙትን ፡ ሕልም ፡ አትስሙ ።
፱ በስሜ ፡ ሐሰተኛ ፡ ትንቢትን ፡ ይናገሩላችኋልና ፤
፲ እኔም ፡ አልላክኋቸውም ። እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላልና ፡— ሰባው ፡ ዓመት ፡ በባቢሎን ፡
በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ እጐበኛችኋለሁ ፥ ወደዚህም ፡
ስፍራ ፡ እመልሳችሁ ፡ ዘንድ ፡ መልካሚቱን ፡
፲፩ ቃሌን ፡ እፈጽምላችኋለሁ ። ለእናንተ ፡ የማስ
በትን ፡ አሳብ ፡ እኔ ፡ አውቃለሁ ፤ ፍጻሜና ፡
ተስፋ ፡ እሰጣችሁ ፡ ዘንድ ፡ የሰላም ፡ አሳብ ፡
፲፪ ነው ፡ እንጂ ፡ የክፉ ፡ ነገር ፡ አይደለም ። እናን
ተም ፡ ትጠሩኛላችሁ ፥ ሄዳችሁም ፡ ወደ ፡ እኔ ፡
፲፫ ትጸልያላችሁ ፥ እኔም ፡ እሰማችኋለሁ ። እና
ንተ ፡ ትሹኛላችሁ ፥ በፍጹም ፡ ልባችሁም ፡ ከሻ
፲፬ ችሁኝ ፡ ታገኙኛላችሁ ። ከእናንተም ፡ ዘንድ ፡
እገኛለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፥ ምርኮአች
ሁንም ፡ እመልሳለሁ ፥ ከአሕዛብም ፡ ሁሉ ፡
ዘንድ ፡ እናንተንም ፡ ከሳደድሁበት ፡ ስፍራ ፡
ሁሉ ፡ እሰበስባችኋለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብ
ሔር ፤ እናንተንም ፡ ለምርኮ ፡ ወዳፈለስሁበት ፡
ስፍራ ፡ እመልሳችኋለሁ ።

፲፭ እናንተም ፡— እግዚአብሔር ፡ በባቢሎን ፡
፲፮ ነቢያትን ፡ አስነሥቶልናል ፡ ብላችኋልና ፤ እግ
ዚአብሔር ፡ በዳዊት ፡ ዙፋን ፡ ስለ ፡ ተቀመጠ ፡
ንጉሥ ፡ ከእናንተም ፡ ጋር ፡ ስላልተማረኩት ፡
ወንድሞቻችሁ ፥ በዚህች ፡ ከተማ ፡ ስለሚኖሩ ፡
፲፯ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፥ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— የሠራዊት ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ፥
ሰይፍንና ፡ ራብን ፡ ቸነፈርንም ፡ እሰድድባቸዋ
ለሁ ፥ ከክፋቱም ፡ የተነሣ ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ እን
ደማይቻል ፡ እንደ ፡ ክፉ ፡ በለስ ፡ አደርጋቸዋ
፲፰ ለሁ ። በሰይፍም ፡ በራብም ፡ በቸነፈርም ፡ አሳድ
ዳቸዋለሁ ፥ ባሳደድሁባቸውም ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡
ዘንድ ፡ ለጥላቻና ፡ ለመደነቂያ ፡ ለማፍዋጫም ፡
ለመሰደቢያም ፡ እንዲሆኑ ፡ በምድር ፡ መንግሥ
ታት ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ ለመበተን ፡ አሳልፌ ፡ እሰ
፲፱ ጣቸዋለሁ ። ይህም ፡ የሆነው ፡ ቃሌን ፡ ስላል
ሰሙ ፡ ነው ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ በማለዳ ፡
ተነሥቼ ፡ ባሪያዎቼን ፡ ነቢያትን ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡
ሰድጃለሁና ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ አልሰማችሁም ፥
፳ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ስለዚህ ፡ ከኢየሩሳ
ሌም ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ የሰደድኋችሁ ፡ ምርኮ
ኞች ፡ ሁሉ ፡ ሆይ ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
ስሙ ።

፳፩ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ በስሜ ፡ ሐሰተኛ ፡ ትንቢትን ፡ ስለሚ
ናገሩላችሁ ፡ ስለ ፡ ቆላያ ፡ ልጅ ፡ ስለ ፡ አክዓብና ፡
ስለ ፡ መዕሤያ ፡ ልጅ ፡ ስለ ፡ ሴዴቅያስ ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እነሆ ፥ በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ በናቡከ
ደነፆር ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣቸዋለሁ ፥ በዓይ
፳፪ ኖቻችሁም ፡ ፊት ፡ ይገድላቸዋል ። ከእነርሱም ፡
የተነሣ ፡ በባቢሎን ፡ ያሉ ፡ የይሁዳ ፡ ምርኮኞች ፡
ሁሉ ፡— የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ በእሳት ፡ እንደ ፡
ጠበሳቸው ፡ እንደ ፡ ሴዴቅያስና ፡ እንደ ፡ አክ
ዓብ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያድርግህ ፡ የምትባል ፡
እርግማንን ፡ ያነሣሉ ፤ እኔም ፡ አውቃለሁ ፡ ምስ
፳፫ ክርም ፡ ነኝ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። በእስ
ራኤል ፡ ዘንድ ፡ ስንፍና ፡ አድርገዋልና ፥ ከባል
ንጀሮቻቸውም ፡ ሚስቶች ፡ ጋር ፡ አመንዝረ
ዋልና ፥ ያላዘዝኋቸውንም ፡ ቃል ፡ በስሜ ፡ በሐ
ሰት ፡ ተናግረዋልና ።

፳፬ ለኔሔላማዊው ፡ ለሸማያ ፡ እንዲህ ፡ በል ፡—
፳፭ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚ

እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በኢየሩሳሌም ፡ ወዳለው ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ÷ ወደ ፡ ካህኑም ፡ ወደ ፡ መዕሤያ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ሶፎንያስ ÷ ወደ ፡ ካህናቱም ፡ ሁሉ ፡ ደብዳቤዎችን ፡ በስምህ ፡ እንዲህ ፡ ፳፮ ስትል ፡ ልከሃል ፡— እያበደ ፡ ትንቢት ፡ የሚናገርን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በእግር ፡ ግንድና ፡ በዛንጅር ፡ ታኖረው ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ እንድትሆን ፡ እግዚአብሔር ፡ በካህኑ ፡ በዮዳሄ ፡ ፳፯ ፋንታ ፡ ካህን ፡ አድርጎሃል ። አሁንስ ፡ ትንቢት ፡ ተናጋሪውን ፡ የዓናቶቱን ፡ ሰው ፡ ኤርምያስን ፡ ፳፰ ስለ ፡ ምን ፡ አትዘልፈውም ? እርሱ ፡— ምርኮው ፡ የረዘመ ፡ ነውና ፡ ቤት ፡ ሥርታችሁ ፡ ተቀመጡ ÷ አታክልትንም ፡ ተክላችሁ ፡ ፍሬዋን ፡ ብሉ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ልኮአልና ። ፳፱ ካህኑም ፡ ሶፎንያስ ፡ ይህን ፡ ደብዳቤ ፡ በነቢዩ ፡ ፴ በኤርምያስ ፡ ጆሮ ፡ አነበበው ። የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ፴፩ መጣ ፡— እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ኔሔላማዊው ፡ ስለ ፡ ሸማያ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡ ብለህ ፡ ወደ ፡ ምርኮኞች ፡ ሁሉ ፡ ላክ ፡— እኔ ፡ ሳልልከው ፡ ሸማያ ፡ ትንቢት ፡ ተናግሮላችኋልና ÷ በሐሰትም ፡ እን ፴፪ ድትታመኑ ፡ አድርጎአችኋልና ፡ ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ ኔሔላማዊውን ፡ ሸማያንና ፡ ዘሩን ፡ እቀጣለሁ ፤ እኔም ፡ የማደርግላችሁን ፡ መልካምን ፡ ነገር ፡ የሚያይ ፡ ሰው ፡ በመካከላችሁ ፡ አይኖርላቸውም ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

፩ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ ፪ የመጣው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የነገርሁህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ በመጽሐፍ ፡ ጻፍ ። ፫ እነሆ ÷ የሕዝቤን ፡ የእስራኤልንና ፡ የይሁዳን ፡ ምርኮ ፡ የምመልስበት ፡ ዘመን ፡ ይመጣልና ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ለአባቶቻቸውም ፡ ወደ ፡ ሰጠኋት ፡ ምድር ፡ እመልሳቸዋለሁ ÷ እነርሱም ፡ ይገዙአታል ።

፬ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ እስራኤልና ፡ ስለ ፡ ይሁዳ ፡ ፭ የተናገረው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— የሚያስፈራ ፡ ድምፅ ፡ ሰምተናል ፤ የፍርሃት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የሰላም ፡ ፮ አይደለም ። ጠይቁ ÷ ወንድ ፡ ይወልድ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ተመልከቱ ፤ ስለ ፡ ምን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ወላድ ፡ እጁን ፡ በወገቡ ፡ ላይ ፡ አድርጎ ፡ ፊቱም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ጥቁረት ፡ ተለውጦ ፡ አየሁ ? ፯ ወዮ ! ያ ፡ ቀን ፡ ታላቅ ፡ ነውና ÷ እርሱንም ፡ የሚመስል ፡ የለምና ፤ ያ ፡ የያዕቆብ ፡ መከራ ፡ ዘመን ፡ ፰ ነው ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ ይድናል ። በዚያ ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ÷ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ ቀንበርን ፡ ከአንገትህ ፡ እሰብራለሁ ÷ እስራትህንም ፡ እበጥሳለሁ ÷ ከእ ፱ ንግዲህ ፡ ወዲህም ፡ ለሌላ ፡ አትገዛም ፤ ለአምላካቸው ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ ለማስነሣላቸው ፡ ለንጉሣቸው ፡ ለዳዊትም ፡ ይገዛሉ ፡ እንጂ ፡ ሌሎች ፡ አሕዛብ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ አይገዙአቸውም ።

፲ እነሆ ÷ አንተን ፡ ከሩቅ ፡ ዘርህንም ፡ ከምርኮ ፡ አገር ፡ አድናለሁና ፡ ባሪያዬ ፡ ያዕቆብ ፡ ሆይ ÷ አትፍራ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ÷ አንተም ፡ እስራኤል ፡ ሆይ ÷ አትደንግጥ ፤ ያዕቆብም ፡ ይመለሳል ፡ ያርፍማል ፡ ተዘልሎም ፡ ይቀመጣል ፤ ፲፩ ማንም ፡ አያስፈራውም ። አድንህ ፡ ዘንድ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነኝና ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ አንተንም ፡ የበተንሁባቸውን ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሜ ፡ አጠፋለሁ ÷ አንተን ፡ ግን ፡ ፈጽሜ ፡ አላጠፋህም ፤ በመጠን ፡ እቀጣሃለሁ ÷ ያለ ፡ ቅጣትም ፡ ከቶ ፡ አልተውህም ።

፲፪ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ስብራትህ ፡ የማይፈወስ ፡ ቍስልህም ፡ ክፉ ፡ ነው ። ፲፫ ትጠገን ፡ ዘንድ ፡ ክርክርህን ፡ የሚፈርድልህ ፡ የለም ÷ ቍስልህንም ፡ የሚፈውስ ፡ መድኃ ፲፬ ኒት ፡ የለህም ። ውሽሞችህ ፡ ሁሉ ፡ ረስተውሃል ፡ አይፈልጉህምም ፤ በደልህ ፡ ታላቅ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ኃጢአትህም ፡ ስለ ፡ በዛ ÷ በጠላት ፡ ማቍሰልና ፡ በጨካኝ ፡ ቅጣት ፡ አቍስዬሃለሁና ። ፲፭ ሕመምህ ፡ የማይፈወስ ፡ ሆኖአልና ፡ ስለ ፡ ስብራትህ ፡ ለምን ፡ ትጮኻለህ ? በደልህ ፡ ታላቅ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ኃጢአትህም ፡ ስለ ፡ በዛ ÷ ይህን ፡ አድር ፲፮ ጌብሃለሁ ። ስለዚህ ፡ የሚውጡህ ፡ ሁሉ ፡ ይዋጣሉ ÷ ጠላቶችህም ፡ ሁላቸው ፡ ይማረካሉ ፤ የዘረፉህም ፡ ይዘረፋሉ ÷ የበዘበዙህንም ፡ ሁሉ ፡ ፲፯ ለመበዝበዝ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣለሁ ። እኔ ፡ ጤናህን ፡ እመልስልሃለሁ ፡ ቍስልህንም ፡ እፈውሳለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ማንም ፡ የማይሻት ÷ የተጣለች ፡ ጽዮን ፡ ብለው ፡ ጠርተውሻልና ።

፲፰ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ የያዕቆብን ፡ ድንኳን ፡ ምርኮ ፡ እመልሳለሁ ÷ ለማደሪያውም ፡ እራራለሁ ፤ ከተማይቱም ፡ በጉብታዋ ፡ ላይ ፡ ትሠራለች ÷ አዳራሹም ፡ እንደ ፡ ፲፱ ዱሮው ፡ የሰው ፡ መኖሪያ ፡ ይሆናል ። ከእርሱም ፡ ዘንድ ፡ የምስጋናና ፡ የዘፋኞች ፡ ድምፅ ፡ ይወጣል ፤ እኔም ፡ አበዛቸዋለሁ ፡ አያንሱምም ÷ እኔም ፡ አከብራቸዋለሁ ፡ ታናሽም ፡ አይሆኑም ። ፳ ልጆቻቸውም ፡ እንደ ፡ ቀድሞ ፡ ይሆናሉ ÷ ማኅበራቸውም ፡ በፊቴ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፤ የሚያስጨንቋቸውንም ፡ ሁሉ ፡ እቀጣለሁ ። ፳፩ አለቃቸው ፡ ከእነርሱ ፡ ውስጥ ፡ ይሆናል ÷ ገዢአቸውም ፡ ከመካከላቸው ፡ ይወጣል ፤ እኔ ፡ አቀርበዋለሁ ፡ እርሱም ፡ ይቀርባል ፤ ይህስ ፡ ባይሆን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ለመቅረብ ፡ የሚደፍር ፡ ፳፪ ማን ፡ ነው ? ይላል ፡ እግዚአብሔር ። እናንተም ፡ ሕዝብ ፡ ትሆኑኛላችሁ ፡ እኔም ፡ አምላክ ፡ እሆናችኋለሁ ።

፳፫ እነሆ ÷ የእግዚአብሔር ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ÷ እርሱም ፡ ቍጣው ÷ የሚያገለባብጥ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ወጥቶአል ፤ የዓመፀኞችንም ፡ ራስ ፡ ይገ ፳፬ ለባብጣል ። የእግዚአብሔር ፡ ጽኑ ፡ ቍጣ ፡ የል

ቡን ፡ አሳብ ፡ ሠርቶ ፡ እስኪፈጽም ፡ ድረስ ፡ አይመለስም ፤ በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ ታስተውሉታላችሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፩ ።

፩ በዚያን ፡ ዘመን ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ÷ ለእስራኤል ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ አምላክ ፡ እሆናቸዋለሁ ፡ እነርሱም ፡ ሕዝብ ፡ ይሆኑኛል ። ፪ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እስራኤል ፡ ማረፊያ ፡ ሊሻ ፡ በሄደ ፡ ጊዜ ፡ ከሰይፍ ፡ የተረፈው ፡ ሕዝብ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ሞገስ ፡ አገኘ ። ፫ እግዚአብሔርም ፡ ከሩቅ ፡ ተገለጠልኝ ፡ እንዲህም ፡ አለኝ ፡— በዘላለም ፡ ፍቅር ፡ ወድጄሻለሁ ፤ ስለዚህ ፡ በቸርነት ፡ ሳብሁሽ ። ፬ የእስራኤል ፡ ድንግል ፡ ሆይ ÷ እንደ ፡ ገና ፡ እሠራሻለሁ ፡ አንቺም ፡ ትሠሪያለሽ ፤ እንደ ፡ ገናም ፡ ከበሮሽን ፡ እንሥተሽ ፡ ከዘፋኞች ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ዘፈን ፡ ትወጫለሽ ። ፭ እንደ ፡ ገናም ፡ በሰማርያ ፡ ተራሮች ፡ ላይ ፡ የወይን ፡ ቦታዎችን ፡ ትተክሊአለሽ ፤ አትክልተኞች ፡ ይተክላሉ ፡ በፍሬውም ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ። ፮ በኤፍሬምም ፡ ተራሮች ፡ ላይ ፡ ያሉ ፡ ጠባቆች ፡— ተነሡ ÷ ወደ ፡ ጽዮን ፡ ወደ ፡ አምላካችን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንውጣ ፡ ብለው ፡ የሚጮኹበት ፡ ቀን ፡ ይመጣልና ።

፯ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— ስለ ፡ ያዕቆብ ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ስለ ፡ አሕዛብም ፡ አለቆች ፡ እልል ፡ በሉ ፤ አውሩ ÷ አመስግኑ ፡— እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ የእስራኤልን ፡ ቅሬታ ፡ አድኖአል ፡ በሉ ። ፰ እነሆ ÷ ከሰሜን ፡ አገር ፡ አመጣቸዋለሁ ÷ ከምድርም ፡ ዳርቻ ፡ እሰበስባቸዋለሁ ÷ በመካከላቸውም ፡ ዕውሩና ፡ አንካሳው ፡ ያረገዘችና ፡ የወለደችም ፡ በአንድነት ፤ ታላቅ ፡ ጉባኤ ፡ ሆነው ፡ ወደዚህ ፡ ይመለሳሉ ። ፱ በልቅሶ ፡ ወጡ ፡ እኔም ፡ በማጽናናት ፡ አመጣቸዋለሁ ፤ በወንዝ ፡ ዳር ፡ በቅን ፡ መንገድ ፡ አስኬዳቸዋለሁ ÷ በእርሱም ፡ አይሰናከሉም ፤ እኔ ፡ ለእስራኤል ፡ አባት ፡ ነኝና ÷ ኤፍሬምም ፡ በኵሬ ፡ ነውና ።

፲ አሕዛብ ፡ ሆይ ÷ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስሙ ÷ በሩቅም ፡ ላሉ ፡ ደሴቶች ፡ አውሩና ፡— እስራኤልን ፡ የበተነ ፡ እርሱ ፡ ይሰበስበዋል ÷ እረኛም ፡ መንጋውን ፡ እንደሚጠብቅ ፡ ይጠብቀዋል ፡ በሉ ። ፲፩ እግዚአብሔር ፡ ያዕቆብን ፡ ተቤዥቶታል ÷ ከበረቱበትም ፡ እጅ ፡ አድኖታል ። ፲፪ ይመጣሉ ፡ በጽዮንም ፡ ተራራ ፡ እልል ፡ ይላሉ ፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በጎነት ÷ ወደ ፡ እህልና ፡ ወደ ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡ ወደ ፡ ዘይትም ÷ ወደ ፡ በጎችና ፡ ወደ ፡ ላሞች ፡ ይሰበሰባሉ ፤ ነፍሳቸውም ፡ እንደ ፡ ረካች ፡ ገነት ፡ ትሆናለች ÷ ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ አያዝኑም ። ፲፫ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ድንግሊቱ ፡ በዘፈን ፡ ደስ ፡ ይላታል ÷ ጐበዛዝቱና ፡ ሽማግሌዎቹም ፡ በአንድ ፡ ላይ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፤ ልቅሶአቸውንም ፡ ወደ ፡ ደስታ ፡ እመልሳለሁ ÷ አጽናናቸውማለሁ ÷ ከኅዘናቸውም ፡ ደስ ፡ አሰኛቸዋለሁ ። ፲፬ የካህናቱንም ፡ ነፍስ ፡ በብዛት ፡ አረካታለሁ ፡ ሕዝቤም ፡ በጎነቴን ፡ ይጠግባል ።

፲፭ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የዋይታና ፡ የመራራ ፡ ልቅሶ ፡ ድምፅ ፡ በራማ ፡ ተሰማ ፤ ራሔል ፡ ስለ ፡ ልጆችዋ ፡ አለቀሰች ፤ የሉምና ፡ ስለ ፡ ልጆችዋ ፡ መጽናናትን ፡ እንቢ ፡ አለች ። ፲፮ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ድምፅሽን ፡ ከልቅሶ ፡ ዓይንሽንም ፡ ከእንባ ፡ ከልክዪ ፤ ለሥራሽ ፡ ዋጋ ፡ ይሆናልና ÷ ከጠላትም ፡ ምድር ፡ ይመለሳሉ ። ፲፯ ለፍጻሜሽም ፡ ተስፋ ፡ አለ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ÷ ልጆችሽም ፡ ወደ ፡ ዳርቻቸው ፡ ይመለሳሉ ። ፲፰ ኤፍሬም ፡— ቀጣሽኝ ፡ እኔም ፡ እንዳልተገራ ፡ ወይፈን ፡ ተቀጣሁ ፤ አንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላኬ ፡ ነህና ፡ መልሰኝ ፡ እኔም ፡ እመለሳለሁ ። ፲፱ ከተመለስሁ ፡ በኋላ ፡ ተጸጸትሁ ÷ ከተገሠጽሁም ፡ በኋላ ፡ ጭኔን ፡ ጸፋሁ ፤ የብላቴንነቴንም ፡ ስድብ ፡ ተሸክሜአለሁና ፡ አፈርሁ ÷ ተዋረድሁም ፡ ብሎ ፡ ሲያለቅስ ፡ ሰማሁ ። ፳ በእውነት ፡ ኤፍሬም ፡ ለእኔ ፡ የከበረ ፡ ልጅ ፡ ነውን ? ወይስ ፡ የተወደደ ፡ ሕፃን ፡ ነውን ? በእርሱ ፡ ላይ ፡ በተናገርሁ ፡ ቍጥር ፡ አስበዋለሁ ፤ ስለዚህ ፡ አንጀቴ ፡ ታወከችለት ፡ ርኅራኄም ፡ እራራለታለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፳፩ ለራስሽ ፡ የመንገድ ፡ ምልክት ፡ አድርጊ ÷ መንገድንም ፡ የሚመሩ ፡ ዓምዶችን ፡ ትከዪ ÷ ልብሽንም ፡ ወደ ፡ ሄድሽበት ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡ ጥርጊያው ፡ አቅኚ ፤ አንቺ ፡ የእስራኤል ፡ ድንግል ፡ ሆይ ÷ ተመለሺ ÷ ወደ ፡ እነዚህም ፡ ወደ ፡ ከተሞችሽ ፡ ተመለሺ ። ፳፪ አንቺ ፡ ከዳተኛ ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ እስከ ፡ መቼ ፡ ትቅበዘበዢለሽ ? እግዚአብሔር ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ ፈጥሮአልና ፡ ሴት ፡ ወንድን ፡ ትከብባለች ።

፳፫ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ምርኮአቸውን ፡ በመለስሁ ፡ ጊዜ ፡ በይሁዳ ፡ አገር ፡ በከተሞችዋ ፡— የጽድቅ ፡ ማደሪያ ፡ ሆይ ÷ የቅድስና ፡ ተራራ ፡ ሆይ ÷ እግዚአብሔር ፡ ይባርክህ ፡ የሚልን ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ይናገራሉ ። ፳፬ በይሁዳ ፡ ከተሞችና ፡ በአገሩ ፡ ሁሉ ፡ ከገበሬዎችና ፡ መንጋን ፡ ይዘው ፡ ከሚዞሩ ፡ ጋር ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ይገኛሉ ። ፳፭ የደከመችውን ፡ ነፍስ ፡ አርክቻለሁና ÷ ያዘነችውንም ፡ ነፍስ ፡ ሁሉ ፡ አጥግቤአለሁና ። ፳፮ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ነቃሁ ፡ ተመለከትሁም ÷ እንቅልፌም ፡ ጣፋጭ ፡ ሆነልኝ ።

፳፯ የእስራኤልን ፡ ቤትና ፡ የይሁዳን ፡ ቤት ፡ በሰው ፡ ዘርና ፡ በእንስሳ ፡ ዘር ፡ የምዘራበት ፡ ዘመን ÷ እነሆ ÷ ይመጣል ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፳፰ እንዲህም ፡ ይሆናል ፤ አፈርሳቸውና ፡ ክፉ ፡ አደርግባቸው ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተጋሁባቸው ÷ እንዲሁ ፡ እሠራቸውና ፡ እተክላቸው ፡ ዘንድ ፡ እተጋለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፳፱ በዚያ ፡ ዘመን ፡ ሰው ፡ ዳግመኛ ፡ እንዲህ ፡ አይልም ፡— አባቶች ፡ ጨርቋ ፡ የወይን ፡ ፍሬ ፡ በሉ ÷ የልጆችም ፡ ጥር

፴፤ ሶች ፡ ጠረሱ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በገዛ ፡
በደሉ ፡ ይሞታል ፤ መራራውን ፡ የወይን ፡ ፍሬ ፡
የሚበላ ፡ ሁሉ ፡ ጥርሶቹ ፡ ይጠርሳሉ ።

፴፩፤ እነሆ ፥ ከእስራኤል ፡ ቤትና ፡ ከይሁዳ ፡ ቤት ፡
ጋር ፡ አዲስ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ የምገባበት ፡
ወራት ፡ ይመጣል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤
፴፪፤ ከግብጽ ፡ አገር ፡ አወጣቸው ፡ ዘንድ ፡ እጃቸ
ውን ፡ በያዝሁበት ፡ ቀን ፡ ከአባቶቻቸው ፡ ጋር ፡
እንደ ፡ ገባሁት ፡ ያለ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አይደለም ፤
እነርሱ ፡ በኪዳኔ ፡ አልጸኑምና ፥ እኔም ፡ ቸል ፡
፴፫፤ አልኋቸው ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ከእነዚያ ፡
ወራት ፡ በኋላ ፡ ከእስራኤል ፡ ቤት ፡ ጋር ፡ የም
ገባው ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ይህ ፡ ነውና ፥ ይላል ፡ እግ
ዚአብሔር ፤ ሕጌን ፡ በልቡናቸው ፡ አኖራለሁ ፥
በልባቸውም ፡ እጽፈዋለሁ ፤ እኔም ፡ አምላክ ፡
እሆናቸዋለሁ ፡ እነርሱም ፡ ሕዝብ ፡ ይሆኑኛል ።
፴፬፤ እያንዳንዱ ፡ ሰው ፡ ባልንጀራውን ፥ እያንዳን
ዱም ፡ ወንድሙን ፡— እግዚአብሔርን ፡ እወቅ ፡
ብሎ ፡ አያስተምርም ፤ ከታናሹ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ታላቁ ፡ ድረስ ፡ ሁሉ ፡ ያውቁኛልና ፥ ይላል ፡
እግዚአብሔር ። በደላቸውን ፡ እምራቸዋለ
ሁና ፥ ኃጢአታቸውንም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
አላስብምና ።

፴፭፤ ስሙ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ የሚባል ፥ ፀሐይን ፡
በቀን ፡ የጨረቃንና ፡ የከዋክብትን ፡ ሥርዓት ፡
በሌሊት ፡ ብርሃን ፡ አድርጎ ፡ የሚሰጥ ፥ እንዲ
ተምሙም ፡ የባሕርን ፡ ሞገዶች ፡ የሚያናውጥ ፡
፴፮፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ይህ ፡ ሕግ ፡
ከፊቴ ፡ ቢወገድ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፥ በዚ
ያን ፡ ጊዜ ፡ ደግሞ ፡ የእስራኤል ፡ ዘር ፡ በፊቴ ፡
፴፯፤ ሕዝብ ፡ እንዳይሆን ፡ ለዘላለም ፡ ይቀራል ። እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ሰማይ ፡ በላይ ፡
ቢከነዳ ፥ የምድርም ፡ መሠረት ፡ በታች ፡ ቢመ
ረመር ፥ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ስላደረጉት ፡ ነገር ፡
ሁሉ ፡ የእስራኤልን ፡ ዘር ፡ ሁሉ ፡ እጥላለሁ ፥
ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፴፰፤ ከሐናንኤል ፡ ግንብ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ማዕ
ዘኑ ፡ በር ፡ ድረስ ፡ ከተማ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
የሚሠራበት ፡ ዘመን ፥ እነሆ ፥ ይመጣል ፥ ይላል ፡
፴፱፤ እግዚአብሔር ። የተለካበትም ፡ ገመድ ፡ ወደ ፡
ጋሬብ ፡ ኮረብታ ፡ በቀጥታ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ይሄ
፵፤ ዳል ፥ ወደ ፡ ጎዓም ፡ ይዞራል ። የሬሳም ፡ ሸለቆ ፡
ሁሉ ፡ የአመድም ፡ እርሻ ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ቄድ
ሮን ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ እስ
ካለው ፡ እስከ ፡ ፈረስ ፡ በር ፡ ማዕዘን ፡ ድረስ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ ፡ ይሆናል ፤ ከእን
ግዲህም ፡ ወዲህ ፡ ለዘላለም ፡ አይነቀልም ፡ አይ
ፈርስምም ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

፩፤ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በሴዴቅያስ ፡ በአሥረኛው ፡
ዓመት ፥ በናቡከደነፆር ፡ በአሥራ ፡ ስምንተ
ኛው ፡ ዓመት ፥ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡
፪፤ ኤርምያስ ፡ የመጣው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። በዚ
ያን ፡ ጊዜም ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ሠራዊት ፡
ኢየሩሳሌምን ፡ ከብቦ ፡ ነበር ፤ ነቢዩም ፡ ኤርም
ያስ ፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ቤት ፡ በነበረው ፡ በግ
፫፤ ዞት ፡ ቤት ፡ አደባባይ ፡ ታስሮ ፡ ነበር ። የይሁዳ ፡
ንጉሥ ፡ ሴዴቅያስ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አስጠብ
ቆት ፡ ነበርና ፡— ስለ ፡ ምን ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡
ትንቢት ፡ ትናገራለህ ፡— እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ፥ ይህችን ፡ ከተማ ፡ ለባቢ
ሎን ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣለሁ ፡ እር
፬፤ ሱም ፡ ይይዛታል ፤ የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ ሴዴ
ቅያስ ፡ በእውነት ፡ በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡
አልፎ ፡ ይሰጣል ፥ አፍ ፡ ለአፍም ፡ ይናገረ
ዋል ፥ ዓይኑም ፡ ዓይኑን ፡ ያያል ፡ እንጂ ፡ ከከለ
፭፤ ዳውያን ፡ እጅ ፡ አያመልጥም ፤ እርሱም ፡ ሴዴ
ቅያስን ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ያፈልሰዋል ፥ እኔም ፡
እስክጐበኘው ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ ይኖራል ፥ ይላል ፡
እግዚአብሔር ፤ ከከለዳውያን ፡ ጋር ፡ ብትዋጉ ፡
ምንም ፡ አትረቡም ።

፮፤ ኤርምያስም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— የእግዚአብ
ሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡—
፯፤ እነሆ ፥ የአጐትህ ፡ የሰሎም ፡ ልጅ ፡ አናምኤል ፡
ወደ ፡ አንተ ፡ መጥቶ ፡— ትገዛው ፡ ዘንድ ፡ መቤ
ዡቱ ፡ የአንተ ፡ ነውና ፡ በዓናቶት ፡ ያለውን ፡ እር
፰፤ ሻዬን ፡ ግዛ ፡ ይልሃል ። እንደ ፡ እግዚአብሔርም ፡
ቃል ፡ የአጐቴ ፡ ልጅ ፡ አናምኤል ፡ እኔ ፡ ወዳለ
ሁበት ፡ ወደ ፡ ግዞቱ ፡ ቤት ፡ አደባባይ ፡ መጥቶ ፡—
በብንያም ፡ አገር ፡ በዓናቶት ፡ ያለውን ፡ እርሻ
ዬን ፥ እባክህ ፥ ግዛ ፤ ርስቱ ፡ የአንተ ፡ ነውና ፥
መቤዡቱም ፡ የአንተ ፡ ነውና ፤ ለአንተ ፡ ግዛው ፡
አለኝ ። ይህም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንደ ፡
፱፤ ሆነ ፡ አወቅሁ ። በዓናቶትም ፡ ያለውን ፡ እርሻ ፡
ከአጐቴ ፡ ልጅ ፡ ከአናምኤል ፡ ገዛሁ ፥ አሥራ ፡
፲፤ ሰባት ፡ ሰቅል ፡ ብርም ፡ መዘንሁለት ። በው
ሉም ፡ ወረቀት ፡ ላይ ፡ ፈረምሁ ፡ አተምሁትም ፥
ምስክሮችንም ፡ ጠርቼ ፡ ብሩን ፡ በሚዛን ፡ መዘን
፲፩፤ ሁለት ። የታተመውንና ፡ የተከፈተውን ፡ የውል ፡
፲፪፤ ወረቀት ፡ ወሰድሁ ፤ የአጐቴም ፡ ልጅ ፡ አናም
ኤል ፥ የውሉንም ፡ ወረቀት ፡ የፈረሙ ፡ ምስክ
ሮች ፥ በግዞትም ፡ ቤት ፡ አደባባይ ፡ የተቀመጡ ፡
አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ እያዩ ፡ የውሉን ፡ ወረቀት ፡
ለመሕሤያ ፡ ልጅ ፡ ለኔርያ ፡ ልጅ ፡ ለባሮክ ፡ ሰጠ
፲፫፤ ሁት ። በፊታቸውም ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ ባሮክን ፡
፲፬፤ አዘዝሁት ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ብዙ ፡
ቀን ፡ ይጠበቁ ፡ ዘንድ ፡ የታተመውንና ፡ የተከ
ፈተውን ፡ ይህን ፡ የውል ፡ ወረቀት ፡ ወስደህ ፡
፲፭፤ በሸክላ ፡ ዕቃ ፡ ውስጥ ፡ አኑራቸው ። የእስራ
ኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— ሰዎች ፡ በዚህች ፡
ምድር ፡ ቤትንና ፡ እርሻን ፡ የወይን ፡ ቦታንም ፡
እንደ ፡ ገና ፡ ይገዛሉ ።

፲፮፤ ለኔርያ ፡ ልጅ ፡ ለባሮክም ፡ የውሉን ፡ ወረ
ቀት ፡ ከሰጠሁት ፡ በኋላ ፥ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ ወደ ፡
፲፯፤ እግዚአብሔር ፡ ጸለይሁ ፡— አቤቱ ፡ ጌታ ፡ እግ

ዚአብሔር፡ሆይ÷እነሆ÷አንተ፡ሰማይንና፡
ምድርን፡በታላቅ፡ኃይልህና፡በተዘረጋች፡
ክንድህ፡ፈጥረሃል÷ከአንተም፡የሚያቅት፡
፲፰፡ ነገር፡የለም። ለብዙ፡ሺህ፡ምሕረት፡ታደ
ርጋለህ÷የአባቶችንም፡በደል፡ከእነርሱ፡
በኋላ፡በልጆቻቸው፡ብብት፡ትመልሳለህ፤
ስምህ፡ታላቅና፡ኃያል፡አምላክ፡የሠራ
፲፱፡ ዊት፡ጌታ፡እግዚአብሔር፡ነው። በምክር፡
ታላቅ፡በሥራም፡ብርቱ፡ነህ፤ለሁሉም፡
እንደ፡መንገዱና፡እንደ፡ሥራው፡ፍሬ፡
ትሰጥ፡ዘንድ፡ዓይኖችህ፡በአዳም፡ልጆች፡
፳፡ መንገድ፡ሁሉ፡ተገልጠዋል። እስከ፡ዛሬም፡
ድረስ፡ምልክትንና፡ድንቅን፡ነገር፡በግብጽ፡
ምድር፡ደግሞም፡በእስራኤልና፡በሌሎች፡
ሰዎች፡መካከል፡አድርገሃል÷እንደ፡ዛሬም፡
፳፩፡ ለአንተ፡ስም፡አድርገሃል። በምልክትና፡
በድንቅ፡ነገር፤በብርቱ፡እጅና፡በተዘረጋች፡
ክንድ፡በታላቅም፡ግርማ፡ሕዝብህን፡እስራ
፳፪፡ ኤልን፡ከግብጽ፡ምድር፡አወጣህ። ትሰጣቸ
ውም፡ዘንድ፡ለአባቶቻቸው፡የማልህላቸውን፡
ምድር÷ወተትና፡ማርንም፡የምታፈስሰውን፡
፳፫፡ ምድር÷ሰጠሃቸው፤ እነርሱም፡ገብተው፡
ወረሱአት፤ነገር፡ግን፡ቃልህን፡አልሰሙም፡
በሕግህም፡አልሄዱም÷ያደርጉም፡ዘንድ፡
ካዘዝሃቸው፡ሁሉ፡ምንም፡አላደረጉም፤ስለ
ዚህ፡ይህን፡ክፉ፡ነገር፡ሁሉ፡አመጣህባቸው።
፳፬፡ እነሆ፡የአፈር፡ድልድል÷ሊይዙአትም፡
እስከ፡ከተማይቱ፡ድረስ፡ቀርበዋል፤ከሰይፍና፡
ከራብ፡ከቸነፈርም፡የተነሣ፡ከተማይቱ፡ለሚ
ዋጉአት፡ለከለዳውያን፡እጅ፡ተሰጥታለች÷
የተናገርኸውም፡ሆኖአል፤እነሆም÷አንተ፡
፳፭፡ ታየዋለህ። አንተም÷ጌታ፡እግዚአብሔር፡
ሆይ፡— እርሻውን፡በብር፡ግዛ፡ምስክሮች
ንም፡ጥራ፡አልኸኝ፤ከተማይቱ፡ግን፡ለከለ
ዳውያን፡እጅ፡ተሰጥታለች።
፳፮፡ የእግዚአብሔርም፡ቃል፡ወደ፡ኤርምያስ፡
፳፯፡ እንዲህ፡ሲል፡መጣ፡— እነሆ÷እኔ፡የሥጋ፡
ለባሽ፡ሁሉ፡አምላክ፡እግዚአብሔር፡ነኝ፤
፳፰፡ በውኑ፡እኔን፡የሚያቅተኝ፡ነገር፡አለን? ስለ
ዚህ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— እነሆ÷
ይህችን፡ከተማ፡ለከለዳውያን፡እጅና፡ለባ
ቢሎን፡ንጉሥ፡ለናቡከደነፆር፡እጅ፡አሳልፌ፡
፳፱፡ እሰጣለሁ÷እርሱም፡ይይዛታል። ይህችን፡
ከተማ፡የሚወጉ፡ከለዳውያን፡መጥተው፡
በእሳት፡ያነድዱአታል÷ያስቈጡኝም፡ዘንድ፡
በሰገነታቸው፡ላይ፡ለበኣል፡ካጠኑባቸው÷
ለሌሎችም፡አማልክት፡የመጠጥን፡ቍርባን፡
ካፈሰሱባቸው፡ቤቶች፡ጋር፡ያቃጥሉአታል።
፴፡ የእስራኤል፡ልጆችና፡የይሁዳ፡ልጆች፡
ከታናሽነታቸው፡ጀምሮ፡በፊቴ፡ክፉ፡ነገርን፡
ብቻ፡አድርገዋልና፤የእስራኤልም፡ልጆች፡
እኔን፡በእጃቸው፡ሥራ፡ከማስቈጣት፡በቀር፡
፴፩፡ ሌላ፡ሥራ፡አላደረጉምና። ከፊቴ፡አስወግ
ዳት፡ዘንድ፡ይህች፡ከተማ፡ከሠሩአት፡ቀን፡
ጀምሮ፡እስከ፡ዛሬ፡ድረስ፡ቍጣዬንና፡መዓ
፴፪፡ ቴን፡ለማነሣሣት፡ሆናለችና፤ ይህም፡እኔን፡
ያስቈጡኝ፡ዘንድ÷እነርሱና፡ነገሥታቶቻ
ቸው፡አለቆቻቸውም፡ካህናቶቻቸውም፡ነቢ
ያቶቻቸውም፡የይሁዳም፡ሰዎች፡በኢየሩሳሌ
ምም፡የሚኖሩ÷ስላደረጉት፡ስለ፡እስራኤል፡
ልጆችና፡ስለ፡ይሁዳ፡ልጆች፡ክፋት፡ሁሉ፡ነው።
፴፫፡ ፊታቸውንም፡ሳይሆን፡ጀርባቸውን፡ወደ፡
እኔ፡መለሱ፤እኔም፡በማለዳ፡ተነሥቼ፡ሳስ
ተምራቸው፡ተግሣጽን፡ይቀበሉ፡ዘንድ፡
፴፬፡ አልሰሙም። ያረከሱትም፡ዘንድ፡ስሜ፡በተ
ጠራበት፡ቤት፡ውስጥ፡ርኵሰታቸውን፡አኖሩ።
፴፭፡ ይሁዳን፡ወደ፡ኃጢአት፡እንዲያገቡት÷ይህ
ንን፡ርኵሰት፡ያደርጉ፡ዘንድ÷እኔ፡ያላዘዝ
ሁትንና፡በልቤ፡ያላሰብሁትን፡ነገር÷ወንዶ
ችና፡ሴቶች፡ልጆቻቸውን፡ለሞሎክ፡በእሳት፡
ያሳልፉ፡ዘንድ፡በሄኖም፡ልጅ፡ሸለቆ፡ውስጥ፡
ያሉትን፡የበኣልን፡የኮረብታውን፡መስገጃ
ዎች፡ሠሩ።
፴፮፡ አሁን፡እንግዲህ፡የእስራኤል፡አምላክ፡
እግዚአብሔር፡አንተ፡ስለ፡እርስዋ፡— በሰይ
ፍና፡በራብ፡በቸነፈርም፡ለባቢሎን፡ንጉሥ፡
እጅ፡ተሰጥታለች፡ስለምትላት፡ከተማ፡እን
፴፯፡ ዲህ፡ይላል፡— እነሆ÷በቍጣዬና፡በመዓቴ፡
በታላቅም፡መቅሠፍቴ፡እነርሱን፡ካሳደድሁ
ባት፡አገር፡ሁሉ፡እሰበስባቸዋለሁ÷ወደዚ
ህም፡ስፍራ፡እመልሳቸዋለሁ÷ተዘልለውም፡
፴፰፡ እንዲኖሩ፡አደርጋለሁ፤ እነርሱም፡ሕዝብ፡
ይሆኑኛል፡እኔም፡አምላክ፡እሆናቸዋለሁ።
፴፱፡ ለእነርሱም፡ከእነርሱም፡በኋላ፡ለልጆቻቸው፡
መልካም፡ይሆንላቸው፡ዘንድ፡ለዘላለም፡
እንዲፈሩኝ፡አንድ፡ልብና፡አንድ፡መንገድ፡
፵፡ እሰጣቸዋለሁ። ለእነርሱም፡ከማደርገው፡በጎ
ነት፡አልመለስም፡ስል÷ከእነርሱ፡ጋር፡የዘ
ላለምን፡ቃል፡ኪዳን፡እገባለሁ፤ከእኔም፡
ዘንድ፡ፈቀቅ፡እንዳይሉ፡መፈራቴን፡በልባ
፵፩፡ ቸው፡ውስጥ፡አኖራለሁ። ለእነርሱም፡መል
ካምን፡በማድረግ፡ደስ፡ይለኛል፡በእውነትም፡
በፍጹም፡ልቤና፡በፍጹም፡ነፍሴ፡በዚህች፡
፵፪፡ ምድር፡እተክላቸዋለሁ። እግዚአብሔር፡እን
ዲህ፡ይላልና፡— ይህን፡እጅግ፡ክፉ፡ነገር፡
ሁሉ፡በዚህ፡ሕዝብ፡ላይ፡እንዳመጣሁ÷እን
ዲሁ፡የተናገርሁላቸውን፡በጎነት፡ሁሉ፡አመ
፵፫፡ ጣላቸዋለሁ። እናንተም፡— ያለ፡ሰውና፡ያለ፡
እንስሳ፡ያለች፡ባድማ፡ናት÷ለከለዳውያ
ንም፡እጅ፡ተሰጥታለች፡በምትሉአት፡ምድር፡
፵፬፡ እርሻን፡ይገዛሉ። ምርኮኞቻቸውንም፡እመል
ሳለሁና፡በብንያም፡አገር፡በኢየሩሳሌምም፡
ዙሪያ፡ባሉ፡ስፍራዎች÷በይሁዳም፡ከተሞች፡
በደጋውም፡ባሉ፡ከተሞች፡በቈላውም፡ባሉ፡
ከተሞች፡በደቡብም፡ባሉ፡ከተሞች÷ሰዎች፡
እርሻውን፡በብር፡ይገዛሉ፡በውሉም፡ወረ
ቀት፡ፈርመው፡ያትማሉ፡ምስክሮችንም፡
ይጠራሉ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፫ ።

፩ ኤርምያስ ፡ ገና ፡ በግዞት ፡ ቤት ፡ አደባባይ ፡
ታስሮ ፡ ሳለ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ሁለተኛ ፡
፪ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣለት ፡— ስሙ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ የሆነ ÷ ያደረገው ፡ እግዚአብሔር ÷
ያጸናውም ፡ ዘንድ ፡ የሠራው ፡ እግዚአብሔር ፡
፫ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ወደ ፡ እኔ ፡ ጩኽ ÷ እኔም ፡
እመልስልሃለሁ ፤ አንተም ፡ የማታውቀውን ፡
፬ ታላቅና ፡ ኃይለኛ ፡ ነገርን ፡ አሳይሃለሁ ። የእስ
ራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአፈር ፡ ድል
ድልና ፡ ለምሽግ ፡ ስለ ፡ ፈረሱ ፡ ስለዚህች ፡ ከተማ ፡
ቤቶች ÷ ስለ ፡ ይሁዳም ፡ ነገሥታት ፡ ቤቶች ፡
፭ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— ከለዳውያን ፡ ለመዋጋት ፡
መጥተዋል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በቍጣዬና ፡ በመዓቴ ፡
በገደልኋቸው ፡ ሰዎች ፡ ሬሳዎች ፡ ሊሞሉአቸው ፡
ነው ÷ ስለ ፡ ክፋታቸው ፡ ሁሉ ፡ ፊቴን ፡ ከዚ
፮ ህች ፡ ከተማ ፡ ሰውሬአለሁና ። እነሆ ÷ ፈውስ
ንና ፡ መድኃኒትን ፡ አመጣላታለሁ ÷ እፈውሳቸ
ውማለሁ ፤ የሰላምንና ፡ የእውነትን ፡ ብዛት ፡ እገ
፯ ልጥላቸዋለሁ ። የይሁዳን ፡ ምርኮና ፡ የእስራ
ኤልንም ፡ ምርኮ ፡ እመልሳለሁ ÷ ቀድሞም ፡
፰ እንደ ፡ ነበሩ ፡ አድርጌ ፡ እሠራቸዋለሁ ። እኔ
ንም ፡ ከበደሉበት ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ አነጻቸዋ
ለሁ ፡ እኔንም ፡ የበደሉኝን ፡ ያመፁብኝንም ፡
፱ ኃጢአታቸውን ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡ እላለሁ ። ይህ
ችም ፡ ከተማ ፡ እኔ ፡ የምሠራላቸውን ፡ በጎነት ፡
ሁሉ ፡ በሚሰሙ ፡ እኔም ፡ ስላመጣሁላቸው ፡
በጎነትና ፡ ሰላም ፡ ሁሉ ፡ በሚፈሩና ፡ በሚደነ
ግጡ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ለደስታ ፡ ስም ፡
ለምስጋናም ፡ ለክብርም ፡ ትሆናለች ።

፲ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እናንተ ፡—
ያለ ፡ ሰውና ፡ ያለ ፡ እንስሳ ፡ ያለች ፡ ባድማ ፡ ናት ፡
በምትሉአት ፡ በዚህች ፡ ስፍራ ÷ የሚቀመጥበ
ቸው ፡ በሌላ ÷ ያለ ፡ ሰውና ፡ ያለ ፡ እንስሳ ፡
ባድማ ፡ በሆኑ ፡ በይሁዳ ፡ ከተሞችና ፡ በኢየ
፲፩ ሩሳሌም ፡ አደባባይ ÷ የሐሤት ፡ ድምፅና ፡ የደ
ስታ ፡ ድምፅ ÷ የወንድ ፡ሙሽራ ፡ ድምፅና ፡
የሴት ፡ ሙሽራ ፡ ድምፅ ፡— እግዚአብሔር ፡
ቸር ፡ ነውና ÷ ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ፡
የሠራዊትን ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስ
ግኑ ፡ የሚሉ ፡ ድምፅ ÷ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡
ቤት ፡ የምስጋናን ፡ መሥዋዕት ፡ የሚያመጡት ፡
ድምፅ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ይሰማል ። የምድርን ፡
ምርኮ ፡ ቀድሞ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ አድርጌ ፡ እመል
ሳለሁና ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፲፪ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— ባድማ ፡ ሆኖ ÷ ያለ ፡ ሰውና ፡ ያለ ፡ እን
ስሳ ፡ ባለው ፡ በዚህ ፡ ስፍራ ፡ በከተሞችም ፡
ሁሉ ፡ መንጎቻቸውን ፡ የሚያሳርፉት ፡ የእረ
፲፫ ኞች ፡ መኖሪያ ፡ ይሆናል ። በደጋው ፡ ላይ ፡
ባሉ ፡ ከተሞች ፡ በቈላውም ፡ ባሉ ፡ ከተሞች ፡
በደቡብም ፡ ባሉ ፡ ከተሞች ÷ በብንያምም ፡
አገር ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ ዙሪያ ፡ ባሉ ፡ ስፍራ
ዎች ÷ በይሁዳም ፡ ከተሞች ፡ መንጎቹ ፡ በተቈጣ
ጣሪው ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ያልፋሉ ÷ ይላል ፡
እግዚአብሔር ።

፲፬ እነሆ ÷ ስለ ፡ እስራኤል ፡ ቤትና ፡ ስለ ፡ ይሁዳ ፡
ቤት ፡ የተናገርሁትን ፡ መልካም ፡ ቃል ፡ የምፈ
ጽምበት ፡ ዘመን ፡ ይመጣል ÷ ይላል ፡ እግዚአ
፲፭ ብሔር ። በዚያም ፡ ዘመን ፡ በዚያም ፡ ጊዜ ፡ ለዳ
ዊት ፡ የጽድቅን ፡ ቍጥቋጥ ፡ አበቅልለታለሁ ፤
እርሱም ፡ ፍርድንና ፡ ጽድቅን ፡ በምድር ፡ ያደ
፲፮ ርጋል ። በዚያም ፡ ዘመን ፡ ይሁዳ ፡ ይድናል ፡
ኢየሩሳሌምም ፡ ተዘልላ ፡ ትቀመጣለች ፤ የም
ትጠራበትም ፡ ስም ፡— እግዚአብሔር ፡ ጽድቃ
፲፯ ችን ፡ ተብሎ ፡ ነው ። እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላልና ፡— በእስራኤል ፡ ቤት ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡
የሚቀመጥ ፡ ሰው ፡ ከዳዊት ፡ ዘንድ ፡ አይታ
፲፰ ጣም ፤ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ የሚያ
ቀርብ ፡ የእህሉንም ፡ ቍርባን ፡ የሚያቃጥል ፡
ሁልጊዜም ፡ የሚሠዋ ፡ ሰው ፡ ከሌዋውያን ፡ ካህ
ናት ፡ ዘንድ ፡ በእኔ ፡ ፊት ፡ አይታጣም ።

፲፱ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡
፳ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፡— ቀንና ፡ ሌሊት ፡ በወራቱ ፡ እንዳ
ይሆን ፡ የቀን ፡ ቃል ፡ ኪዳኔንና ፡ የሌሊት ፡ ቃል ፡
፳፩ ኪዳኔን ፡ ማፍረስ ፡ ብትችሉ ÷ በዙፋኑ ፡ ላይ ፡
የሚነግሥ ፡ ልጅ ፡ እንዳይሆንለት ፡ ከባሪያዬ ፡
ከዳዊት ፡ ጋር ÷ ከአገልጋዮቼም ፡ ከሌዋውያን ፡
ካህናት ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ ቃል ፡ ኪዳኔ ፡ ደግሞ ፡
፳፪ ይፈርሳል ። የሰማይን ፡ ሠራዊት ፡ መቍጠር ፡
የባሕርንም ፡ አሸዋ ፡ መስፈር ፡ እንደማይቻል ÷
እንዲሁ ፡ የባሪያዬን ፡ የዳዊትን ፡ ዘርና ፡ የሚያ
ገለግሉኝን ፡ ሌዋውያንን ፡ አበዛለሁ ።

፳፫ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ እን
፳፬ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ይህ ፡ ሕዝብ ፡— እግዚአ
ብሔር ፡ የመረጣቸውን ፡ ሁለቱን ፡ ወገን ፡ ጥሎ
አቸዋል ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ አትመለከትምን ?
እንዲሁ ፡ በፊታቸው ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
ሕዝብ ፡ እንዳይሆን ፡ ሕዝቤን ፡ አቃልለዋል ።
፳፭ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የቀንና ፡
የሌሊት ፡ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ የሰማይንና ፡ የምድ
፳፮ ርንም ፡ ሥርዓት ፡ ያላጸናሁ ፡ እንደ ፡ ሆን ÷ እኔም ፡
ደግሞ ፡ በአብርሃምና ፡ በይስሐቅ ፡ በያዕቆብም ፡
ዘር ፡ ላይ ፡ ገዦች ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ከዘሩ ፡ እንዳ
ልወስድ ÷ የያዕቆብንና ፡ የባሪያዬን ፡ የዳዊትን ፡
ዘር ፡ እጥላለሁ ፤ ምርኮአቸውን ፡ እመልሳለ
ሁና ÷ እምራቸውማለሁና ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፬ ።

፩ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆርና ፡ ሠራ
ዊቱ ፡ ሁሉ ፡ ከእጁም ፡ ግዛት ፡ በታች ፡ ያሉ ፡ የም
ድር ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡
ኢየሩሳሌምንና ፡ ከተሞችዋን ፡ ሁሉ ፡ ይወጉ ፡
በነበረ ፡ ጊዜ ÷ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡
፪ ኤርምያስ ፡ የመጣ ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። የእስ
ራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡

ይላል፡— ሂድ፡ለይሁዳም፡ንጉሥ፡ለሴዴቅያስ፡ተናገር፡እንዲህም፡በለው፡— እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— እነሆ÷ይህችን፡ከተማ፡በባቢሎን፡ንጉሥ፡እጅ፡አሳልፌ፡እሰጣለሁ÷በእሳትም፡ያቃጥላታል፤ ፫ አንተም፡በእርግጥ፡ትያዛለህ፡በእጁም፡አልፈህ፡ትሰጣለህ፡እንጂ፡ከእጁ፡አታመልጥም፤ ዓይንህም፡የባቢሎንን፡ንጉሥ፡ዓይን፡ታያለች÷እርሱም፡ከአንተ፡ጋር፡አፍ፡ለአፍ፡ይናገራል÷ወደ፡ባቢሎንም፡ትገባለህ። ፬ ነገር፡ግን÷የይሁዳ፡ንጉሥ፡ሴዴቅያስ፡ሆይ÷የእግዚአብሔርን፡ቃል፡ስማ፤ እግዚአብሔር፡ስለ፡አንተ፡እንዲህ፡ይላል፡— በሰይፍ፡አትሞትም÷ ፭ በሰላም፡ትሞታለህ፡እንጂ፤ ከአንተ፡በፊት፡እንደ፡ነበሩ፡እንደ፡ዱሮ፡ነገሥታት፡እንደ፡አባቶችህ፡መቃጠል÷እንዲሁ፡ያቃጥሉሃልና፡— ወየው! ጌታ፡ሆይ፡እያሉ፡ያለቅሱልሃል፤ እኔ፡ቃልን፡ተናግሬአለሁና÷ይላል፡እግዚአብሔር።

፮፡፯ የባቢሎንም፡ንጉሥ፡ሠራዊት፡ኢየሩሳሌምንና፡የቀሩትን፡የይሁዳን፡ከተሞች፡ሁሉ÷ከተመሸጉት፡ከይሁዳ፡ከተሞች፡የተረፉትን፡ለኪሶንና፡ዓዜቃን፡በወጋ፡ጊዜ÷ነቢዩ፡ኤርምያስ፡ይህን፡ቃል፡ሁሉ፡ለይሁዳ፡ንጉሥ፡ለሴዴቅያስ፡በኢየሩሳሌም፡ነገረው።

፰፡፱ ሰው፡ሁሉ፡ዕብራዊ፡የሆነውን፡ወንድ፡ባሪያውንና፡ዕብራዊት፡የሆነች፡ሴት፡ባሪያውን፡አርነት፡እንዲያወጣ÷አይሁዳዊ፡ወንድሙንም፡ማንም፡እንዳይገዛ÷ስለ፡አርነታቸው፡አዋጅ፡እንዲነገር፡ንጉሡ፡ሴዴቅያስ፡በኢየሩሳሌም፡ከነበሩ፡ሕዝብ፡ሁሉ፡ጋር፡ቃል፡ኪዳን፡ካደረገ፡በኋላ÷ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ወደ፡ኤርምያስ፡የመጣው፡ቃል፡ይህ፡ነው። ፲ ሰው፡ሁሉ፡ወንድ፡ባሪያውንና፡ሴት፡ባሪያውን፡አርነት፡እንዲያወጣ፡ከእንግዲህ፡ወዲህም፡ማንም፡እንዳይገዛቸው፡ወደ፡ቃል፡ኪዳኑ፡የገቡ፡አለቆች፡ሁሉና፡ሕዝቡ፡ሁሉ፡ሰሙ፤ ፲፩ አርነትም፡አወጡአቸው። ነገር፡ግን፡ከዚያ፡በኋላ፡ተመልሰው፡አርነት፡ያወጡአቸውን፡ወንዶችና፡ሴቶች፡ባሪያዎቻቸውን፡አስመለሱ÷ወንዶችና፡ሴቶች፡ባሪያዎችም፡አድርገው፡ገዙአቸው። ፲፪ ስለዚህ፡የእግዚአብሔር፡ቃል፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ወደ፡ኤርምያስ፡ ፲፫ እንዲህ፡ሲል፡መጣ፡— የእስራኤል፡አምላክ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— አባቶቻችሁን፡ከባርነት፡ቤት፡ከግብጽ፡አገር፡ባወጣኋቸው፡ቀን፡ከእነርሱ፡ጋር፡እንዲህ፡ብዬ፡ ፲፬ ቃል፡ኪዳን፡አደረግሁ፡— ሰባት፡ዓመት፡በተፈጸመ፡ጊዜ÷የተሸጠላችሁን፡ስድስትም፡ዓመት፡የተገዛላችሁን፡ዕብራዊ፡ወንድማችሁን፡እያንዳንዳችሁ፡አርነት፡ታወጡታላችሁ÷እያንዳንዱም፡ያወጣዋል፤ አባቶቻችሁ፡ግን፡አልሰሙኝም፡ጆሮአቸውንም፡አላዘነበሉም። ፲፭ እናንተም፡ዛሬ፡ተመልሳችሁ፡ሰው፡ሁሉ፡ባልንጀራውን፡አርነት፡ለማውጣት፡አዋጅ፡በመንገር፡ለዓይኔ፡ደስ፡የሚያሰኘን፡ነገር፡አድርጋችሁ፡ነበር÷በስሜም፡በሚጠራበት፡ቤት፡ውስጥ፡በፊቴ፡ቃል፡ኪዳን፡አድርጋችሁ፡ነበር። ፲፮ ነገር፡ግን፡ተመልሳችሁ፡ስሜን፡አስነቀፋችሁ÷እያንዳንዳችሁም፡በፈቃዳቸው፡እንዲሄዱ፡አርነት፡ያወጣችኋቸውን፡ወንድና፡ሴት፡ባሪያዎቻችሁን፡አስመለሳችሁ÷ወንዶችና፡ሴቶች፡ባሪያዎችም፡እንዲሆኑላችሁ፡ገዛችኋቸው።

፲፯ ስለዚህ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— ሰው፡ሁሉ፡ለወንድሙና፡ለባልንጀራው፡የአርነት፡አዋጅ፡ለመንገር፡እኔን፡አልሰማችሁም፤ እነሆ÷እኔ፡ለሰይፍና፡ለቸነፈር፡ለራብም፡የአርነት፡አዋጅ፡እናገርባችኋለሁ÷ይላል፡እግዚአብሔር፤ በምድርም፡መንግሥታት፡ሁሉ፡መካከል፡እንድትበተኑ፡አደርጋችኋለሁ። ፲፰ ቃል፡ኪዳኔንም፡የተላለፉትን፡ሰዎች÷እንበሳውንም፡ቈርጠው፡በቍራጩ፡መካከል፡ባለፉ፡ጊዜ፡በፊቴ፡ያደረጉትን፡ ፲፱ የቃል፡ኪዳንን፡ቃል፡ያልፈጸሙትን÷የይሁዳን፡አለቆችና፡የኢየሩሳሌምን፡አለቆች፡ጃንደረቦችን፡ካህናትንም፡በእንበሳም፡ቍራጭ፡መካከል፡ያለፉትን፡የአገሩን፡ሕዝብ፡ሁሉ÷ ፳ ለጠላቶቻቸው፡እጅ፡ነፍሳቸውንም፡ለሚሹአት፡እጅ፡አሳልፌ፡እሰጣለሁ፤ ሬሳቸውም፡ለሰማይ፡ወፎችና፡ለምድር፡አራዊት፡መብል፡ይሆናል። ፳፩ የይሁዳንም፡ንጉሥ፡ሴዴቅያስንና፡አለቆቹን፡ለጠላቶቻቸው፡እጅ፡ነፍሳቸውንም፡ለሚሹአት፡እጅ፡ከእናንተም፡ለተመለሱት፡ለባቢሎን፡ንጉሥ፡ሠራዊት፡እጅ፡አሳልፌ፡እሰጣለሁ። ፳፪ እነሆ÷አዝዛለሁ÷ይላል፡እግዚአብሔር÷ወደዚህችም፡ከተማ፡እመልሳቸዋለሁ፤ እርስዋንም፡ይወጋሉ፡ይይዙአትማል፡በእሳትም፡ያቃጥሉአታል፤ የይሁዳንም፡ከተሞች፡ሰው፡የሌለበት፡ባድማ፡አደርጋቸዋለሁ።

## ምዕራፍ፡፴፭።

፩ በይሁዳ፡ንጉሥ፡በኢዮስያስ፡ልጅ፡በኢዮአቄም፡ዘመን፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ወደ፡ኤርምያስ፡የመጣ፡ቃል፡ይህ፡ነው፡— ፪ ወደ፡ሬካባውያን፡ቤት፡ሄደህ፡ተናገራቸው÷ወደ፡እግዚአብሔርም፡ቤት፡ከጓዳዎቹ፡ወደ፡አንዲቱ፡አግባቸው፡የወይን፡ጠጅም፡አጠጣቸው። ፫ የከባስንን፡ልጅ፡የኤርምያስን፡ልጅ፡ያእዛንያን፡ወንድሞቹንም፡ልጆቹንም፡ሁሉ፡የሬካባውያንን፡ወገን፡ሁሉ፡ወሰድኋቸው፤ ፬ ወደ፡እግዚአብሔርም፡ቤት፡በበረኛው፡በሰሎም፡ልጅ፡በመዕሴያ፡ጓዳ፡በላይ፡ባለው፡በአለቆች፡ጓዳ፡አጠገብ፡ወዳለው፡ወደ፡እግዚአብሔር፡ሰው፡ወደ፡ጌዴልያ፡ልጅ፡ወደ፡ሐናን፡ልጆች፡ጓዳ፡አገባኋቸው። ፭ በሬካባውያንም፡ልጆች፡ፊት፡የወይን፡ጠጅ፡

የሞላባቸውን ፡ ማድጋዎችንና ፡ ጽዋዎችን ፡ አኑሬ ፡— የወይኑን ፡ ጠጅ ፡ ጠጡ ፡ አልኋቸው ። ፮ እነርሱ ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አሉ ፡— የወይኑን ፡ ጠጅ ፡ አንጠጣም ፥ አባታችን ፡ የሬካብ ፡ ልጅ ፡ ኢዮናዳብ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዝዞናልና ፡— እናንተና ፡ ልጆቻችሁ ፡ ለዘላለም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ አትጠጡ ። ፯ በምትኖሩበት ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ እንድትኖሩ ፥ በዕድሜአችሁ ፡ ሙሉ ፡ በድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ተቀመጡ ፡ እንጂ ፡ ቤትን ፡ አትሥሩ ፥ ዘርንም ፡ አትዝሩ ፥ ወይንም ፡ አትትከሉ ፥ አንዳችም ፡ አይሁንላችሁ ። ፰ እኛም ፡ የአባታችንን ፡ የሬካብ ፡ ልጅ ፡ የኢዮናዳብን ፡ ቃል ፡ ባዘዘን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ታዝዘናል ፤ እኛም ፡ ሚስቶቻችንም ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችንም ፡ ዕድሜአችንን ፡ ሙሉ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ አልጠጣንም ፤ ፱ የምንቀመጥበትንም ፡ ቤት ፡ አልሠራንም ፤ የወይን ፡ በቃና ፡ እርሻ ፡ ዘርም ፡ የለንም ፤ ፲ በድንኳንም ፡ ውስጥ ፡ ተቀምጠናል ፥ ታዝዘናል ፥ አባታችንም ፡ ኢዮናዳብ ፡ ያዘዘንን ፡ ሁሉ ፡ አድርገናል ። ፲፩ ነገር ፡ ግን ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ወደዚህች ፡ ምድር ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡— ኑ ፡ ከከለዳውያን ፡ ሠራዊትና ፡ ከሶርያ ፡ ሠራዊት ፡ ፊት ፡ የተነሣ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እንሂድ ፡ አልን ፤ እንዲሁም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተቀመጥን ።

፲፪ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ ፲፫ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ሂድና ፡ ለይሁዳ ፡ ሰዎችና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለሚቀመጡ ፡ ተናገር ፡ እንዲህም ፡ በላቸው ፡— ቃሌን ፡ ትሰሙ ፡ ዘንድ ፡ ተግሣጽን ፡ አትቀበሉምን ? ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፲፬ የሬካብ ፡ ልጅ ፡ ኢዮናዳብ ፡ ልጆቹ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ እንዳይጠጡ ፡ ያዘዛቸው ፡ ቃል ፡ ተፈጸመ ፤ ለአባታቸውም ፡ ትእዛዝ ፡ ታዝዘዋልና ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ አይጠጡም ፤ እኔም ፡ በማለዳ ፡ ተነሥቼ ፡ ተናግሬአችኋለሁ ፤ ተናገርሁ ፥ ሆኖም ፡ አልሰማችሁኝም ። ፲፭ ደግሞም ፡— እያንዳንዳችሁ ፡ ከክፉ ፡ መንገዳችሁ ፡ ተመለሱ ፥ ሥራችሁንም ፡ አሳምሩ ፥ ታመልኩአቸውም ፡ ዘንድ ፡ ሌሎችን ፡ አማልክት ፡ አትከተሉ ፥ ለእናንተና ፡ ለአባቶቻችሁም ፡ በሰጠሁት ፡ ምድር ፡ ትቀመጣላችሁ ፡ እያልሁ ፡ በማለዳ ፡ ተነሥቼ ፡ ባሪያዎቼን ፡ ነቢያትን ፡ ሁሉ ፡ ልኬባችሁ ፡ ነበር ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ጆሮአችሁን ፡ አላዘነበላችሁም ፡ እኔንም ፡ አልሰማችሁኝም ። ፲፮ የሬካብ ፡ ልጅ ፡ የኢዮናዳብ ፡ ልጆች ፡ አባታቸው ፡ ያዘዛቸውን ፡ ትእዛዝ ፡ ፈጽመዋልና ፥ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ግን ፡ አልሰማኝምና ፡ ፲፯ ስለዚህ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ፥ በተናገርኋቸው ፡ ጊዜ ፡ አልሰሙምና ፥ በጠራኋቸውም ፡ ጊዜ ፡ አልመለሱልኝምና ፡ የተናገርሁባቸውን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ በሚቀመጡ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አመጣባቸዋለሁ ።

፲፰ ኤርምያስም ፡ ሬካባውያንን ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ለአባታችሁ ፡ ለኢዮናዳብ ፡ ትእዛዝ ፡ ታዝዛችኋልና ፥ ትእዛዙንም ፡ ሁሉ ፡ ጠብቃችኋልና ፥ ያዘዛችሁንም ፡ ፈጽማችኋልና ፡ ፲፱ ስለዚህ ፡ በፊቴ ፡ የሚቆም ፡ ሰው ፡ ከሬካብ ፡ ልጅ ፡ ከኢዮናዳብ ፡ ወገን ፡ ለዘላለም ፡ አይታጣም ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፮ ።

፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ በኢዮአቄም ፡ በአራተኛው ፡ ዓመት ፡ ይህ ፡ ቃል ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ መጣ ። ፪ አንድ ፡ የመጽሐፍ ፡ ክርታስ ፡ ውሰድ ፥ ለአንተም ፡ ከተናገርሁበት ፡ ቀን ፡ ከኢዮስያስ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በእስራኤልና ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ በአሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የተናገርሁህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ጻፍበት ። ፫ ምናልባት ፡ የይሁዳ ፡ ቤት ፡— እኔ ፡ አደርግባቸዋለሁ ፡ ያልሁትንና ፡ ያሰብሁትን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ይሰሙ ፡ ይሆናል ፥ ከክፉ ፡ መንገዳቸው ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ እኔም ፡ በደላቸውንና ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ይቅር ፡ እል ፡ ዘንድ ።

፬ ኤርምያስም ፡ የኔርያን ፡ ልጅ ፡ ባሮክን ፡ ጠራ ፥ ባሮክም ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእርሱ ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ከኤርምያስ ፡ አፍ ፡ በመጽሐፉ ፡ ክርታስ ፡ ጻፈ ። ፭ ኤርምያስም ፡ ባሮክን ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ አዘዘው ፡— እኔ ፡ ተግዤአለሁ ፤ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እገባ ፡ ዘንድ ፡ አልችልም ። ፮ አንተ ፡ ግን ፡ ሂድ ፥ ከአፌም ፡ የጻፍኸውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ በጾም ፡ ቀን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በሕዝቡ ፡ ጆሮ ፡ በክርታሱ ፡ አንብብ ፤ ደግሞም ፡ ከከተሞቻቸው ፡ በሚወጡ ፡ በይሁዳ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ጆሮ ፡ አንብበው ። ፯ እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ የተናገረው ፡ ቍጣውና ፡ መዓቱ ፡ ታላቅ ፡ ነውና ፡ ምናልባት ፡ ጸሎታቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ትወድቅ ፡ ይሆናል ፥ ሁሉም ፡ ከክፉ ፡ መንገዱ ፡ ይመለስ ፡ ይሆናል ። ፰ የኔርያም ፡ ልጅ ፡ ባሮክ ፡ ነቢዩ ፡ ኤርምያስ ፡ ያዘዘውን ፡ ሁሉ ፡ አደረገ ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ በመጽሐፉ ፡ አነበበ ።

፱ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ በኢዮአቄም ፡ በአምስተኛው ፡ ዓመት ፡ በዘጠነኛው ፡ ወር ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የተቀመጡ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ከይሁዳም ፡ ከተሞች ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ የመጡ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለመጾም ፡ አዋጅ ፡ ነገሩ ። ፲ ባሮክም ፡ የኤርምያስን ፡ ቃል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በላይኛው ፡ አደባባይ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በአዲሱ ፡ በር ፡ መግቢያ ፡ ባለው ፡ በጸሐፊው ፡ በሳፋን ፡ ልጅ ፡ በገማርያ ፡ ጓዳ ፡ በሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ጆሮ ፡ በመጽሐፉ ፡ አነበበ ።

፲፩ የሳፋንም ፡ ልጅ ፡ የገማርያ ፡ ልጅ ፡ ሚክያስ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ከመጽሐፉ ፡
፲፪ በሰማ ፡ ጊዜ ÷ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ጸሐ
ፊው ፡ ጓዳ ፡ ወረደ ፤ እነሆም ÷ አለቆች ፡ ሁሉ ÷
ጸሐፊው ፡ ኤሊሳማ ÷ የሽማያ ፡ ልጅ ፡ ድላያ ÷
የዓክቦር ፡ ልጅ ፡ ኤልናታን ÷ የሳፋን ፡ ልጅ ፡
ገማርያ ÷ የሐናንያ ፡ ልጅ ፡ ሴዴቅያስ ፡ አለቆ
፲፫ ቹም ፡ ሁሉ ፡ በዚያ ፡ ተቀምጠው ፡ ነበር ። ሚክ
ያስም ፡ ባሮክ ፡ በሕዝቡ ፡ ጆሮ ፡ በመጽሐፉ ፡ ባነ
በበ ፡ ጊዜ ፡ የሰማውን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ነገራቸው ።
፲፬ አለቆቹም ፡ ሁሉ ፡— በሕዝቡ ፡ ጆሮ ፡ ያነበብኸ
ውን ፡ ክርታስ ፡ በእጅህ ፡ ይዘህ ፡ ና ፡ የሚል ፡
መልእክት ፡ በኵሲ ፡ ልጅ ፡ በሰሌምያ ፡ ልጅ ፡ በና
ታንያ ፡ ልጅ ፡ በይሁዲ ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ ባሮክ ፡
ላኩ ። የኔርያም ፡ ልጅ ፡ ባሮክ ፡ ክርታሱን ፡
፲፭ በእጁ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ መጣ ። እነር
ሱም ፡— እስኪ ፡ ተቀመጥ ÷ በጆሮአችንም ፡
አንብብ ፡ አሉት ። ባሮክም ፡ በጆሮአቸው ፡ አነ
፲፮ በበው ። ቃሉንም ፡ ሁሉ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ፈር
ተው ፡ እርስ ፡ በእርሳቸው ፡ ተመካከሩ ÷ ባሮክ
ንም ፡— ይህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ በእርግጥ ፡ ለን
፲፯ ጉሡ ፡ እንናገራለን ፡ አሉት ። ባሮክንም ፡—
ይህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ከአፉ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡
፲፰ ጻፍኸው ፡ ንገረን ፡ ብለው ፡ ጠየቁት ። ባሮ
ክም ፡— ይህን ፡ ቃል ፡ ከአፉ ፡ ይነግረኝ ፡ ነበር ÷
እኔም ፡ በመጽሐፉ ፡ ላይ ፡ በቀለም ፡ እጽፍ ፡
፲፱ ነበር ፡ ብሎ ፡ መለሰላቸው ። አለቆቹም ፡ ባሮ
ክን ፡— አንተና ፡ ኤርምያስ ፡ ሂዱ ÷ ተሸሸጉ ÷
ወዴትም ፡ እንደ ፡ ሆናችሁ ፡ ማንም ፡ አይወቅ ፡
አሉት ።

፳ ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ወደ ፡ አደባባይ ፡ ገቡ ÷
ክርታሱንም ፡ በጸሐፊው ፡ በኤሊሳማ ፡ ጓዳ ፡
አኑረውት ፡ ነበር ፤ ቃሉንም ፡ ሁሉ ፡ በንጉሡ ፡
፳፩ ጆሮ ፡ ተናገሩ ። ንጉሡም ፡ ክርታሱን ፡ ያመጣ ፡
ዘንድ ፡ ይሁዲን ፡ ላከ ÷ እርሱም ፡ ከጸሐፊው ፡
ከኤሊሳማ ፡ ጓዳ ፡ ወሰደው ፤ ይሁዲም ፡ በንጉ
ሡና ፡ በንጉሡ ፡ አጠገብ ፡ በቆሙት ፡ አለቆች ፡
፳፪ ሁሉ ፡ ጆሮ ፡ አነበበው ። ንጉሡም ፡ በዘጠነ
ኛው ፡ ወር ፡ በክረምት ፡ ቤት ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ÷
በፊቱም ፡ በምድጃ ፡ ውስጥ ፡ እሳት ፡ ይነድድ ፡
፳፫ ነበር ። ይሁዲም ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ አራት ፡
ዓምድ ፡ ያህል ፡ ባነበበ ፡ ቍጥር ÷ ንጉሡ ፡
በካራ ፡ ቀደደው ፤ ክርታሱም ፡ በምድጃ ፡
ውስጥ ፡ ባለው ፡ እሳት ፡ ፈጽሞ ፡ እስኪቃ
ጠል ፡ ድረስ ፡ በምድጃ ፡ ውስጥ ፡ ወዳለው ፡
፳፬ እሳት ፡ ጣለው ። ንጉሡም ፡ ይህንም ፡ ቃል ፡
ሁሉ ፡ የሰሙ ፡ ባሪያዎቹ ፡ ሁሉ ፡ አልፈሩም ፡
፳፭ ልብሳቸውንም ፡ አልቀደዱም ። ነገር ፡ ግን ፡
ኤልናታንና ፡ ድላያ ፡ ገማርያም ፡ ክርታሱን ፡
እንዳያቃጥል ፡ ንጉሡን ፡ ለመኑት ÷ እርሱ ፡
፳፮ ግን ፡ አልሰማቸውም ። ንጉሡም ፡ ጸሐፊውን ፡
ባሮክንና ፡ ነቢዩን ፡ ኤርምያስን ፡ ይይዙ ፡ ዘንድ ፡
የንጉሡን ፡ ልጅ ፡ ይረሕምኤልንና ፡ የዓዝርኤ
ልን ፡ ልጅ ፡ ሠራያን ፡ የዓብድኤልንም ፡ ልጅ ፡
ሰሌምያን ፡ አዘዘ ÷ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ሰወ
ራቸው ።

፳፯ ንጉሡም ፡ ክርታሱንና ፡ ባሮክ ፡ ከኤርምያስ ፡
አፍ ፡ የጻፈውን ፡ ቃል ፡ ካቃጠለ ፡ በኋላ ፡ የእ
ግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ እንዲህ ፡
፳፰ ሲል ፡ መጣ ፡— ዳግመኛም ፡ ሌላ ፡ ክርታስ ፡
ውሰድ ÷ የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮአቄም ፡ ባቃ
ጠለው ፡ ክርታስ ፡ ላይ ፡ የነበረውን ፡ የቀድሞ
፳፱ ውን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ጻፍበት ። የይሁዳንም ፡
ንጉሥ ፡ ኢዮአቄምን ፡ እንዲህ ፡ በለው ፡— እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— አንተ ፡— የባ
ቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ በእርግጥ ፡ ይመጣል ፡ ይህች
ንም ፡ አገር ፡ ያፈርሳታል ፡ ከሰውና ፡ ከእንስ
ሳም ፡ ባዶ ፡ ያደርጋታል ፡ ብለህ ፡ ለምን ፡ ጻፍህ
በት ? ብለህ ፡ ይህን ፡ ክርታስ ፡ አቃጥለሃል ።
፴ ስለዚህም ፡ ስለ ፡ ይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ስለ ፡ ኢዮአ
ቄም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በዳ
ዊት ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ተቀማጭ ፡ አይኖርለትም ÷
ሬሳውም ፡ በቀን ፡ ለትኩሳት ፡ በሌሊትም ፡ ለው
፴፩ ርጭ ፡ ይጣላል ። ስለ ፡ ኃጢአታቸውም ፡ እር
ሱንና ፡ ዘሩን ፡ ባሪያዎቹንም ፡ እቀጣለሁ ፤ እነር
ሱም ፡ አልሰሙምና ፡ የተናገርሁባቸውን ፡ ክፉ ፡
ነገር ፡ ሁሉ ፡ በእነርሱ ፡ ላይና ፡ በኢየሩሳሌም ፡
በሚቀመጡ ፡ በይሁዳም ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ አመ
ጣለሁ ።

፴፪ ኤርምያስም ፡ ሌላ ፡ ክርታስ ፡ ወሰደ ፡ ለኔር
ያም ፡ ልጅ ፡ ለጸሐፊው ፡ ለባሮክ ፡ ሰጠው ፤ እር
ሱም ፡ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮአቄም ፡ በእሳት ፡
ያቃጠለውን ፡ የመጽሐፉን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ከኤር
ምያስ ፡ አፍ ፡ ጻፈበት ÷ ደግሞም ፡ እንደ ፡ ቀድ
ሞው ፡ ያለ ፡ ቃል ፡ ብዙ ፡ ቃል ፡ ተጨመረበት ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፯ ።

፩ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ በይ
ሁዳ ፡ ያነገሠው ፡ የኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ ሴዴቅ
ያስ ፡ በኢዮአቄም ፡ ልጅ ፡ በኢኮንያን ፡ ፋንታ ፡
፪ ነገሠ ። እርሱም ፡ ሆነ ፡ ባሪያዎቹ ፡ የአገሩም ፡
ሕዝብ ፡ በነቢዩ ፡ በኤርምያስ ፡ እጅ ፡ የተናገረ
ውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አልሰሙም ።
፫ ንጉሡም ፡ ሴዴቅያስ ፡— ወደ ፡ አምላካችን ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ ጸልይ ፡ ብሎ ፡
የሰሌምያን ፡ ልጅ ፡ ዮካልንና ፡ ካህኑን ፡ የመዕ
ሤያን ፡ ልጅ ፡ ሶፎንያስን ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡ ወደ ፡
፬ ኤርምያስ ፡ ላከ ። እርሱንም ፡ በግዞት ፡ ቤት ፡ ገና ፡
አላገቡትም ፡ ነበርና ፡ ኤርምያስ ፡ በሕዝቡ ፡
፭ መካከል ፡ ይወጣና ፡ ይገባ ፡ ነበር ። የፈርዖንም ፡
ሠራዊት ፡ ከግብጽ ፡ ወጣ ፤ ኢየሩሳሌምንም ፡
ከብበዋት ፡ የነበሩ ፡ ከለዳውያን ፡ ይህን ፡ ወሬ ፡
በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ።
፮ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡ ወደ ፡
፯ ኤርምያስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የእስራ
ኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— ከእኔ ፡ ትጠይቁ ፡ ዘንድ ፡ የላካችሁን ፡
የይሁዳን ፡ ንጉሥ ፡ እንዲህ ፡ በሉት ፡— እነሆ ÷

ሊረዳችሁ፡የወጣው፡የፈርዖን፡ሠራዊት፡
፯፡ ወደ፡አገሩ፡ወደ፡ግብጽ፡ይመለሳል። ከለዳው
ያንም፡ተመልሰው፡ይህችን፡ከተማ፡ይዋጉ
አታል፡ይይዙአትማል፡በእሳትም፡ያቃጥሉአ
፱፡ ታል። እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— አይ
ሄዱምና፡— ከለዳውያን፡በእርግጥ፡ከእኛ፡
ዘንድ፡ይሄዳሉ፡ብላችሁ፡ራሳችሁን፡አታ
፲፡ ታልሉ። እናንተንም፡የሚዋጉትን፡የከለዳ
ውያንን፡ሠራዊት፡ሁሉ፡ብትመቱት፡ኖሮ ፥
ከእነርሱም፡የተወጉት፡ብቻ፡ቢቀሩ፡ኖሮ ፥
ሁሉ፡እያንዳንዱ፡በድንኳኑ፡ተነሥቶ፡ይህ
ችን፡ከተማ፡በእሳት፡ባቃጠሉአት፡ነበር።
፲፩፡ የከለዳውያንም፡ሠራዊት፡ከፈርዖን፡ሠራ
ዊት፡ፊት፡የተነሣ፡ከኢየሩሳሌም፡በተመ
፲፪፡ ለሰ፡ጊዜ ፥ ኤርምያስ፡በሕዝቡ፡መካከል፡
የርስቱን፡እድል፡ፈንታ፡ከዚያ፡ይቀበል፡
ዘንድ፡ወደ፡ብንያም፡አገር፡ሊሄድ፡ከኢየሩሳ
፲፫፡ ሌም፡ወጣ። በብንያምም፡በር፡በነበረ፡ጊዜ፡
የሐናንያ፡ልጅ፡የሰሌምያ፡ልጅ፡የሪያ፡የተ
ባለ፡የዘበኞች፡አለቃ፡በዚያ፡ነበረ፤ እር
ሱም፡— ወደ፡ከለዳውያን፡መኰብለልህ፡
ነው፡ብሎ፡ነቢዩን፡ኤርምያስን፡ያዘው።
፲፬፡ ኤርምያስም፡— ሐሰት፡ነው፤ ወደ፡ከለዳው
ያን፡መኰብለሌ፡አይደለም፡አለ፤ እርሱ፡ግን፡
አልሰማውም ፥ የሪያም፡ኤርምያስን፡ይዞ፡
፲፭፡ ወደ፡አለቆች፡አመጣው። አለቆችም፡ተቈጥ
ተው፡ኤርምያስን፡መቱት ፥ የጸሐፊውንም፡
የዮናታንን፡ቤት፡የግዞት፡ቤት፡አድርገውት፡
ነበርና፡በዚያ፡አኖሩት።
፲፮፡ ኤርምያስም፡ወደ፡ጕድጓድ፡ቤት፡ወደ፡
ጓዳዎቹ፡ገባ፤ ኤርምያስም፡በዚያ፡ብዙ፡ቀን፡
፲፯፡ ከተቀመጠ፡በኋላ ፥ ንጉሡ፡ሴዴቅያስ፡ልኮ፡
አስመጣው ፥ ንጉሡም፡በቤቱ፡— በውኑ፡ከእ
ግዚአብሔር፡ዘንድ፡የሆነ፡ቃል፡አለን? ብሎ፡
በቈይታ፡ጠየቀው። ኤርምያስም፡— አዎን፡
አለ። ደግሞም፡— በባቢሎን፡ንጉሥ፡እጅ፡
፲፰፡ አልፈህ፡ትሰጣለህ፡አለ። ኤርምያስም፡ደግሞ፡
ንጉሡን፡ሴዴቅያስን፡እንዲህ፡አለው፡—
በግዞት፡ቤት፡የጣላችሁኝ፡አንተን፡ወይስ፡
ባሪያዎችህን፡ወይስ፡ሕዝብህን፡ምን፡በድያ
፲፱፡ ችሁ፡ነው? የባቢሎን፡ንጉሥ፡በእናንተና፡
በዚህች፡አገር፡አይመጣባችሁም፡ብለው፡
ትንቢት፡ይናገሩላችሁ፡የነበሩ፡ነቢያቶቻ
፳፡ ችሁ፡ወዴት፡አሉ? ንጉሡ፡ጌታዬ፡ሆይ ፥
እንድትሰማኝ፡አሁን፡እለምንሃለሁ፤ እባክህ ፥
ልመናዬ፡ወደ፡አንተ፡ይድረስ፤ በዚያ፡እንዳ
ልሞት፡ወደ፡ጸሐፊው፡ወደ፡ዮናታን፡ቤት፡
፳፩፡ አትመልሰኝ። ንጉሡም፡ሴዴቅያስ፡አዘዘ ፥
ኤርምያስንም፡በግዞት፡ቤት፡አደባባይ፡አኖ
ሩት ፥ እንጀራም፡ሁሉ፡ከከተማ፡እስኪጠፋ፡
ድረስ፡ዕለት፡ዕለት፡አንድ፡አንድ፡እንጀራ፡
ከጋጋሪዎች፡መንገድ፡ይሰጡት፡ነበር። እን
ዲሁም፡ኤርምያስ፡በግዞት፡ቤት፡አደባባይ፡
ተቀምጦ፡ነበር።

## ምዕራፍ፡፴፰።

፩፡ ኤርምያስም፡ለሕዝቡ፡ሁሉ፡የተናገረውን፡
ቃል፡የማታን፡ልጅ፡ስፋጥያስ ፥ የጳስኮርም፡
ልጅ፡ጎዶልያስ ፥ የሰሌምያም፡ልጅ፡ዮካል ፥
፪፡ የመልክያም፡ልጅ፡ጳስኮር፡ሰሙ። ኤርምያስ፡
እንዲህ፡ብሎአልና፡— እግዚአብሔር፡እን
ዲህ፡ይላል፡— በዚህች፡ከተማ፡የሚቀመጥ፡
በሰይፍና፡በራብ፡በቸነፈርም፡ይሞታል፤
ወደ፡ከለዳውያን፡ግን፡የሚወጣ፡በሕይወት፡
ይኖራል ፥ ነፍሱም፡እንደ፡ምርኮ፡ትሆንለታ
፫፡ ለች ፥ በሕይወትም፡ይኖራል። እግዚአብ
ሔር፡እንዲህ፡ይላልና፡— ይህች፡ከተማ፡
በባቢሎን፡ንጉሥ፡ሠራዊት፡እጅ፡በእርግጥ፡
፬፡ ትሰጣለች ፥ እርሱም፡ይይዛታል። አለቆቹም፡
ንጉሡን፡— ይህን፡የመሰለውን፡ቃል፡ሲነግራ
ቸው፡በዚህች፡ከተማ፡የቀሩትን፡የሰልፈኞቹን፡
እጅ፡የሕዝቡንም፡ሁሉ፡እጅ፡ያደክማልና፡
ይህ፡ሰው፡እንዲገደል፡እንለምንሃለን፤ ይህ፡
ሰው፡ክፉትን፡እንጂ፡ለዚህ፡ሕዝብ፡ሰላምን፡
፭፡ አይመኝለትምና፡አሉት። ንጉሡም፡ሴዴቅ
ያስ፡— ንጉሡ፡በእናንተ፡ላይ፡ምንም፡ሊያ
ደርግ፡አይችልምና፡እነሆ ፥ በእጃችሁ፡ነው፡
፮፡ አለ። ኤርምያስንም፡ወሰዱት፡በግዞት፡
ቤቱም፡አደባባይ፡ወደ፡ነበረው፡ወደ፡
ንጉሡ፡ልጅ፡ወደ፡መልክያ፡ጕድጓድ፡
ውስጥ፡ጣሉት፤ ኤርምያስንም፡በገመድ፡
አወረዱት። በጕድጓዱም፡ውስጥ፡ጭቃ፡
እንጂ፡ውኃ፡አልነበረበትም፤ ኤርምያስም፡
ወደ፡ጭቃው፡ውስጥ፡ገባ።
፯፡ በንጉሡም፡ቤት፡የነበረው፡ጃንደረባ፡
ኢትዮጵያዊው፡አቤሜሌክ፡ኤርምያስን፡በጕ
ድጓዱ፡ውስጥ፡እንዳኖሩት፡ሰማ። ንጉሡም፡
፰፡ በብንያም፡በር፡ተቀምጦ፡ነበር። አቤሜሌ
ክም፡ከንጉሡ፡ቤት፡ወጥቶ፡ንጉሡን፡እን
፱፡ ዲህ፡አለው፡— ጌታዬ፡ንጉሥ፡ሆይ ፥ እነ
ዚህ፡ሰዎች፡ነቢዩን፡ኤርምያስን፡በጕድጓድ፡
ውስጥ፡በመጣላቸው፡በእርሱ፡ላይ፡በማድ
ረጋቸው፡ሁሉ፡ክፉ፡አድርገዋል፤ በከተማይ
ቱም፡ውስጥ፡እንጀራ፡ስለሌለ፡በዚያ፡በራብ፡
፲፡ ይሞታል። ንጉሡም፡ኢትዮጵያዊውን፡አቤ
ሜሌክን፡— ከአንተ፡ጋር፡ሠላሳ፡ሰዎች፡
ከዚህ፡ውሰድ ፥ ነቢዩም፡ኤርምያስ፡ሳይ
ሞት፡ከጕድጓድ፡አውጣው፡ብሎ፡አዘዘው።
፲፩፡ አቤሜሌክም፡ከእርሱ፡ጋር፡ሰዎችን፡ይዞ፡
ሄደ ፥ ከቤተ፡መዛግብቱም፡በታች፡ወደ፡
ነበረው፡ወደ፡ንጉሥ፡ቤት፡ገባ ፥ ከዚያም፡
አሮጌ፡ጨርቅና፡እላቂ፡ልብስ፡ወሰደ ፥ ወደ፡
ኤርምያስም፡ወደ፡ጕድጓዱ፡ውስጥ፡በገመድ፡
፲፪፡ አወረደው። ኢትዮጵያዊውም፡አቤሜሌክ፡
ኤርምያስን፡— ይህን፡አሮጌ፡ጨርቅና፡እላቂ
ውን፡ልብስ፡በብብትህ፡ከገመዱ፡በታች፡
አድርግ፡አለው፤ ኤርምያስም፡እንዲሁ፡አደ
፲፫፡ ረገ። ኤርምያስንም፡በገመዱ፡ጐተቱት፡

ከጕድጓድም ፡ አወጡት ፥ ኤርምያስም ፡ በግ
ዞት ፡ ቤት ፡ አደባባይ ፡ ተቀመጠ ።

፲፬፤ ንጉሡም ፡ ሴዴቅያስ ፡ ልኮ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ ወደ ፡ ነበረው ፡ ወደ ፡ ሦስተኛው ፡ መግ
ቢያ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ነቢዩን ፡ ኤርምያስን ፡ አስ
መጣው ፤ ንጉሡም ፡ ኤርምያስን ፡— አንዲት ፡
ነገር ፡ እጠይቅሃለሁ ፤ ምንም ፡ አትሸሽገኝ ፡
፲፭፤ አለው ። ኤርምያስም ፡ ሴዴቅያስን ፡— ብነግ
ርህ ፡ በውኑ ፡ አትገድለኝምን ? ብመክርህም ፡
፲፮፤ አትሰማኝም ፡ አለው ። ንጉሡም ፡ ሴዴቅያስ ፡—
ይህችን ፡ ነፍስ ፡ የፈጠረልን ፡ ሕያው ፡ እግዚአ
ብሔርን ! አልገድልህም ፥ ነፍስህንም ፡ ለሚሹ ፡
ለእነዚህ ፡ ሰዎች ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ አልሰጥህም ፡
ብሎ ፡ በቈይታ ፡ ለኤርምያስ ፡ ማለ ።

፲፯፤ ኤርምያስም ፡ ሴዴቅያስን ፡— የእስራኤል ፡
አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡
አለቆች ፡ ብትወጣ ፥ ነፍስህ ፡ በሕይወት ፡ ትኖ
ራለች ፡ ይህችም ፡ ከተማ ፡ በእሳት ፡ አትቃጠ
ልም ፤ አንተም ፡ ቤትህም ፡ በሕይወት ፡ ትኖራ
፲፰፤ ላችሁ ። ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ አለቆች ፡
ባትወጣ ፡ ግን ፥ ይህች ፡ ከተማ ፡ በከለዳውያን ፡
እጅ ፡ ትሰጣለች ፥ በእሳትም ፡ ያቃጥሉአታል ፡
አንተም ፡ ከእጃቸው ፡ አታመልጥም ፡ አለው ።
፲፱፤ ንጉሡም ፡ ሴዴቅያስ ፡ ኤርምያስን ፡— ወደ ፡
ከለዳውያን ፡ በኰበለሉት ፡ በአይሁድ ፡ እጅ ፡
አሳልፈው ፡ ይሰጡኛል ፡ እነርሱም ፡ ያፌዙብ
፳፤ ኛል ፡ ብዬ ፡ እፈራለሁ ፡ አለው ። ኤርምያስም ፡
እንዲህ ፡ አለው ፡— አሳልፈው ፡ አይሰጡህም ።
እኔ ፡ የምነግርህን ፡ የእግዚአብሔርን ቃል ፥
እባክህ ፥ ስማ ፤ ይቀናሃል ፡ ነፍስህም ፡ በሕይ
፳፩፤ ወት ፡ ትኖራለች ። ትወጣ ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡
ብትል ፡ ግን ፥ እግዚአብሔር ፡ ያሳየኝ ፡ ቃል ፡
፳፪፤ ይህ ፡ ነው ። እነሆ ፥ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ቤት ፡
የቀሩትን ፡ ሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡
ንጉሥ ፡ አለቆች ፡ ያወጣሉ ፤ እነዚያም ፡ ሴቶች ፡—
በለምዋሎችህ ፡ አታልለውሃል ፡ አሸንፈውህ
ማል ፤ እግሮችህ ፡ ግን ፡ አሁን ፡ በጭቃ ፡
ውስጥ ፡ ከገቡ ፡ እነርሱ ፡ ከአንተ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡
፳፫፤ ተመልሰዋል ፡ ይላሉ ። ሚስቶችህንና ፡ ልጆ
ችህንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ከለዳውያን ፡ ያወጣሉ ፤
አንተም ፡ በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ ትያዛለህ ፡
እንጂ ፡ ከእጃቸው ፡ አታመልጥም ፤ ይህችም ፡
ከተማ ፡ በእሳት ፡ ትቃጠላለች ።

፳፬፤ ሴዴቅያስም ፡ ኤርምያስን ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡—
ይህን ፡ ቃል ፡ ማንም ፡ አይወቅ ፥ አንተም ፡
፳፭፤ አትሞትም ። አለቆቹ ፡ ግን ፡ እኔ ፡ ከአንተ ፡
ጋር ፡ እንደ ፡ ተነጋገርሁ ፡ ቢሰሙ ፥ ወደ ፡ አን
ተም ፡ መጥተው ፡— ለንጉሡ ፡ ያልኸውን ፡
ንገረን ፡ አትሸሽገንም ፥ እኛም ፡ አንገድልህም ፤
ደግሞ ፡ ንጉሡ ፡ ያለህን ፡ ንገረን ፡ ቢሉህ ፥
፳፮፤ አንተ ፡— በዚያ ፡ እሞት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ዮና
ታን ፡ ቤት ፡ አትመልሰኝ ፡ ብዬ ፡ በንጉሡ ፡
፳፯፤ ፊት ፡ ለመንሁ ፡ በላቸው ። አለቆቹም ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ መጥተው ፡ ጠየቁ ፥ ንጉ
ሡም ፡ እንዳዘዘው ፡ እንደዚህ ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡
ነገራቸው ። ነገሩም ፡ አልተሰማምና ፡ ከእርሱ ፡
፳፰፤ ጋር ፡ መነጋገርን ፡ ተዉ ። ኤርምያስም ፡ ኢየ
ሩሳሌም ፡ እስክ ፡ ተያዘችበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡
በግዞት ፡ ቤት ፡ አደባባይ ፡ ተቀመጠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፱ ።

፩፤ ኢየሩሳሌምም ፡ በተያዘች ፡ ጊዜ ፥ በይሁዳ ፡
ንጉሥ ፡ በሴዴቅያስ ፡ በዘጠነኛው ፡ ዓመት ፡
በአሥረኛው ፡ ወር ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከ
ደነፆርና ፡ ሠራዊቱ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
፪፤ መጥተው ፡ ከበቡአት ፤ በሴዴቅያስም ፡ በአ
ሥራ ፡ አንደኛው ፡ ዓመት ፡ በአራተኛው ፡ ወር ፡
ከወሩም ፡ በዘጠነኛው ፡ ቀን ፡ ከተማይቱ ፡ ተሰ
፫፤ በረች ። የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፥
ኤርጌል ፡ ሳራስር ፥ ሳምጋርናበ ፥ ሠርሰኪም ፥
ራፌስ ፥ ኤርጌል ፡ ሳራስር ፥ ራብማግ ፥ ከቀ
ሩት ፡ ከባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡
ገብተው ፡ በመካከለኛው ፡ በር ፡ ውስጥ ፡ ተቀ
መጡ ።

፬፤ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ሴዴቅያስ ፡ ሰልፈኞቹም ፡
ሁሉ ፡ ባዩአቸው ፡ ጊዜ ፡ ኰበለሉ ፥ በሌሊትም ፡
በንጉሡ ፡ አትክልት ፡ መንገድ ፡ በሁለቱ ፡ ቅጥር ፡
መካከል ፡ ከነበረው ፡ ደጅ ፡ ከከተማይቱ ፡ ወጡ ፤
፭፤ በዓረባም ፡ መንገድ ፡ ወጡ ። የከለዳውያንም ፡
ሠራዊት ፡ ተከታተላቸው ፥ ሴዴቅያስንም ፡ በኢ
ያሪኮ ፡ ሜዳ ፡ አገኙት ፤ ይዘውም ፡ በሐማት ፡
ምድር ፡ ወዳለችው ፡ ወደ ፡ ሪብላ ፡ ወደ ፡ ባቢ
ሎን ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ናቡከደነፆር ፡ አመጡት ፤
እርሱም ፡ ፍርድን ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ተናገረ ።
፮፤ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ የሴዴቅያስን ፡ ልጆች ፡ በዓ
ይኑ ፡ ፊት ፡ በሪብላ ፡ ገደላቸው ፤ የባቢሎንም ፡
ንጉሥ ፡ የይሁዳን ፡ ከበርቴዎች ፡ ሁሉ ፡ ገደለ ።
፯፤ የሴዴቅያስንም ፡ ዓይን ፡ አወጣ ፥ ወደ ፡ ባቢሎ
ንም ፡ ይወስደው ፡ ዘንድ ፡ በሰንሰለት ፡ አሰረው ።
፰፤ ከለዳውያንም ፡ የንጉሡንና ፡ የሕዝቡን ፡ ቤቶች ፡
በእሳት ፡ አቃጠሉ ፥ የኢየሩሳሌምንም ፡ ቅጥር ፡
፱፤ አፈረሱ ። የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡
በከተማይቱ ፡ የቀሩትን ፡ ሕዝብ ፡ ወደ ፡ እር
ሱም ፡ የኰበለሉትን ፡ ሰዎች ፡ የቀረውንም ፡ የሕ
ዝቡን ፡ ቅሬታ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ማረካቸው ።
፲፤ አንዳች ፡ ከሌላቸው ፡ ከሕዝቡ ፡ ድሆች ፡ ግን ፡
የዘበኞቹ ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡ በይሁዳ ፡ አገር ፡
ተዋቸው ፥ የወይኑን ፡ ቦታና ፡ እርሻውን ፡ በዚ
ያን ፡ ጊዜ ፡ ሰጣቸው ።

፲፩፡፲፪፤ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ስለ ፡
ኤርምያስ ፡— ውሰደውና ፡ በመልካም ፡ ተመል
ከተው ፥ የሚሻውንም ፡ ነገር ፡ አድርግለት ፡
እንጂ ፡ ክፉን ፡ ነገር ፡ አታድርግበት ፡ ብሎ ፡ የዘ
፲፫፤ በኞቹን ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳንን ፡ አዘዘ ። የዘበኞ
ቹም ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡ ላከ ፥ ናቡሽዝባ
ንም ፡ ራፋስቂስም ፡ ኤርጌል ፡ ሳራስርም ፡ ራብ
ማግም ፡ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ዋና ፡ ዋና ፡ አለ

፲፬ ቆች ፡ ሁሉ ፡ ላኩ ፤ ኤርምያስንም ፡ ከግዞት ፡
ቤት ፡ አደባባይ ፡ አወጡት ፥ ወደ ፡ ቤቱም ፡ ይወ
ስደው ፡ ዘንድ ፡ ለሳፋን ፡ ልጅ ፡ ለአኪ ቃም ፡
ልጅ ፡ ለጎዶልያስ ፡ ሰጡት ፤ እንዲህም ፡ በሕ
ዝብ ፡ መካከል ፡ ተቀመጠ ።

፲፭ በግዞትም ፡ ቤት ፡ አደባባይ ፡ ታስሮ ፡ ሳለ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ወደ ፡
፲፮ ኤርምያስ ፡ መጣ ፦ ሂድ ፡ ለኢትዮጵያዊውም ፡
ለአቤሜሌክ ፡ እንዲህ ፡ በለው ፦ የእስራኤል ፡
አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፦ እነሆ ፥ ለበጎነት ፡ ሳይሆን ፡
ለክፋት ፡ ቃሌን ፡ በዚህች ፡ ከተማ ፡ ላይ ፡ አመ
ጣለሁ ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ በፊትህ ፡ ይፈጸማል ።
፲፯ በዚያ ፡ ቀን ፡ አድንሃለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብ
ሔር ፤ በምትፈራቸው ፡ ሰዎች ፡ እጅ ፡ አልሰጥ
፲፰ ህም ። ፈጽሜ ፡ አድንሃለሁ ፡ ነፍስህም ፡ እንደ ፡
ምርኮ ፡ ትሆንልሃለች ፡ እንጂ ፡ በሰይፍ ፡ አትወ
ድቅም ፥ በእኔ ፡ ታምነሃልና ፥ ይላል ፡ እግዚአ
ብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፵ ።

፩ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ በተማረኩት ፡ በኢየሩሳሌ
ምና ፡ በይሁዳ ፡ ምርኮኞች ፡ መካከል ፡ የዘበ
ኞቹ ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡ በሰንሰለት ፡ አስሮ ፡
በወሰደው ፡ ጊዜ ፡ ከራማ ፡ ከለቀቀው ፡ በኋላ ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡
፪ የመጣ ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡
ኤርምያስን ፡ ወሰደው ፡ እንዲህም ፡ አለው ፦
አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡
፫ በዚህ ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ ተናገረ ፤ እግዚአብሔ
ርም ፡ አመጣው ፡ እንደ ፡ ተናገረውም ፡ አደ
ረገ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ላይ ፡ ኃጢአት ፡ ሠር
ታችኋልና ፥ ቃሉንም ፡ አልሰማችሁምና ፡ ይህ ፡
፬ ነገር ፡ ሆነባችሁ ። አሁንም ፥ እነሆ ፥ በእጅህ ፡
ካለችው ፡ ሰንሰለት ፡ ዛሬ ፡ ፈታሁህ ። ከእኔ ፡
ጋር ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ መምጣት ፡ መልካም ፡
መስሎ ፡ ቢታይህ ፥ ና ፥ እኔም ፡ በመልካም ፡ አይ
ሃለሁ ፤ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ መምጣት ፡
መልካም ፡ መስሎ ፡ ባይታይህ ፡ ግን ፥ ተቀመጥ ፤
እነሆ ፥ አገሪቱ ፡ ሁሉ ፡ በፊትህ ፡ ናት ፤ ትሄድ ፡
ዘንድ ፡ መልካም ፡ መስሎ ፡ ወደሚታይህ ፡ ደስ ፡
፭ ወደሚያሰኝህም ፡ ስፍራ ፡ ሂድ ። እርሱም ፡
ገና ፡ ሳይመለስ ፦ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ በይ
ሁዳ ፡ ከተሞች ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ሾመው ፡ ወደ ፡
ሳፋን ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ አኪ ቃም ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ጎዶ
ልያስ ፡ ተመለስ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ በሕዝቡ ፡
መካከል ፡ ተቀመጥ ፤ ወይም ፡ ትሄድ ፡ ዘንድ ፡
ደስ ፡ ወደሚያሰኝህ ፡ ስፍራ ፡ ሂድ ፡ አለው ።
የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ስንቅና ፡ ስጦታ ፡ ሰጥቶ ፡
፮ አሰናበተው ። ኤርምያስም ፡ የአኪ ቃም ፡ ልጅ ፡
ጎዶልያስ ፡ ወዳለበት ፡ ወደ ፡ ምጽጳ ፡ ሄደ ፥ ከእ
ርሱም ፡ ጋር ፡ በአገሩ ፡ ውስጥ ፡ በቀሩት ፡ ሕዝብ ፡
መካከል ፡ ተቀመጠ ።
፯ በየሜዳውም ፡ የነበሩት ፡ የጭፍራ ፡ አለቆ
ችና ፡ ሰዎቻቸው ፡ ሁሉ ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡
የአኪ ቃምን ፡ ልጅ ፡ ጎዶልያስን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡
እንደ ፡ ሾመ ፥ ወንዶችንና ፡ ሴቶችን ፡ ልጆች
ንም ፥ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ያልተማረኩትን ፡ የም
ድርን ፡ ድሆች ፥ እንዳስጠበቀ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፥
፰ የናታንያ ፡ ልጅ ፡ እስማኤል ፥ የቃሬያም ፡
ልጆች ፡ ዮሐናንና ፡ ዮናታን ፥ የተንሑሜትም ፡
ልጅ ፡ ሠራያ ፥ የነጦፋዊውም ፡ የዮፌ ፡ ልጆች ፥
የማዕካታዊውም ፡ ልጅ ፡ ያእዛንያ ፡ ከሰዎቻ
ቸው ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ጎዶልያስ ፡ ወደ ፡ ምጽጳ ፡
፱ መጡ ። የሳፋንም ፡ ልጅ ፡ የአኪ ቃም ፡ ልጅ ፡
ጎዶልያስ ፡ ለእነርሱና ፡ ለሰዎቻቸው ፡ እንዲህ ፡
ብሎ ፡ ማለ ፦ ለከለዳውያን ፡ ትገዙ ፡ ዘንድ ፡
አትፍሩ ፤ በምድር ፡ ተቀመጡ ፡ ለባቢሎንም ፡
ንጉሥ ፡ ተገዙ ፥ መልካምም ፡ ይሆንላችኋል ።
፲ እኔም ፥ እነሆ ፥ ወደ ፡ እኛ ፡ በሚመጡት ፡ ከለ
ዳውያን ፡ ፊት ፡ እቆም ፡ ዘንድ ፡ በምጽጳ ፡ እኖ
ራለሁ ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ወይንንና ፡ የበጋ ፡ ፍሬ ፡
ዘይትንም ፡ አከማቹ ፥ በየዕቃችሁም ፡ ውስጥ ፡
ክተቱ ፥ በያዛችኋቸውም ፡ ከተሞቻችሁ ፡ ተቀ
፲፩ መጡ ። በሞዓብም ፡ በአሞንም ፡ ልጆች ፡ መካ
ከል ፡ በኤዶምያስም ፡ በምድርም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡
የነበሩ ፡ አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ የይ
ሁዳን ፡ ቅሬታ ፡ እንዳስቀረ ፥ የሳፋንንም ፡ ልጅ ፡
የአኪ ቃምን ፡ ልጅ ፡ ጎዶልያስን ፡ በላያቸው ፡
፲፪ እንደ ፡ ሾመው ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፥ አይሁድ ፡
ሁሉ ፡ ከተሰደዱበት ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ ተመለሱ ፥
ወደ ፡ ይሁዳም ፡ አገር ፡ ጎዶልያስ ፡ ወዳለበት ፡
ወደ ፡ ምጽጳ ፡ መጡ ፥ ወይንና ፡ የበጋንም ፡
ፍሬ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ አከማቹ ።
፲፫ የቃሬያም ፡ ልጅ ፡ ዮሐናን ፡ በየሜዳውም ፡
የነበሩ ፡ የጭፍራ ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ጎዶ
፲፬ ልያስ ፡ ወደ ፡ ምጽጳ ፡ መጥተው ፦ የአሞን ፡
ልጆች ፡ ንጉሥ ፡ በአሊስ ፡ ይገድልህ ፡ ዘንድ ፡
የናታንያን ፡ ልጅ ፡ እስማኤልን ፡ እንደ ፡ ሰደደ ፡
ታውቃለህን ? አሉት ። የአኪ ቃም ፡ ልጅ ፡ ጎዶ
፲፭ ልያስ ፡ ግን ፡ አላመናቸውም ። የቃሬያም ፡
ልጅ ፡ ዮሐናን ፦ እባክህ ፥ ልሂድ ፤ ማንም ፡
ሳያውቅ ፡ የናታንያን ፡ ልጅ ፡ እስማኤልን ፡ ልግ
ደለው ፤ ወደ ፡ አንተ ፡ የተሰበሰቡ ፡ አይሁድ ፡
ሁሉ ፡ እንዲበተኑ ፡ የይሁዳም ፡ ቅሬታ ፡ እንዲ
ጠፉ ፡ ነፍስህን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይገድላል ? ብሎ ፡
፲፮ በምጽጳ ፡ በቆይታ ፡ ለጎዶልያስ ፡ ተናገረ ። የአ
ኪ ቃም ፡ ልጅ ፡ ጎዶልያስ ፡ ግን ፡ የቃሬያን ፡
ልጅ ፡ ዮሐናንን ፦ በእስማኤል ፡ ላይ ፡ ሐሰት ፡
ተናግረሃልና ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ አታድርግ ፡ አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፩ ።

፩ በሰባተኛውም ፡ ወር ፡ ከመንግሥት ፡ ወገንና ፡
ከንጉሡ ፡ ዋና ፡ ዋና ፡ አለቆች ፡ አንዱ ፡ የኤሊ
ሳማ ፡ ልጅ ፡ የናታንያ ፡ ልጅ ፡ እስማኤል ፡ ከአ
ሥር ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ምጽጳ ፡ ወደ ፡ አኪ
ቃም ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ጎዶልያስ ፡ መጣ ፤ በዚያም ፡
፪ በምጽጳ ፡ በአንድ ፡ ላይ ፡ እንጀራ ፡ በሉ ። የና

ታንያም ፡ ልጅ ፡ እስማኤል ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ አሥሩ ፡ ሰዎች ፡ ተነሥተው ፡ የሳፋንን ፡ ልጅ ፡ የአኪቃምን ፡ ልጅ ፡ ጎዶልያስን ፡ በሰይፍ ፡ መቱ ፥ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ በአገሩ ፡ ላይ ፡ የሾመውን ፡ ገደሉ ። ፫ እስማኤልም ፡ ከጎዶልያስ ፡ ጋር ፡ በምጽጳ ፡ የነበሩትን ፡ አይሁድ ፡ ሁሉ ፥ በዚያም ፡ የተገኙትን ፡ የከለዳውያንን ፡ ሰልፈኞች ፡ ሁሉ ፡ ገደላቸው ።

፬ ጎዶልያስን ፡ ከገደለ ፡ በኋላ ፡ ማንም ፡ ሳያውቅ ፡ ፭ በሁለተኛው ፡ ቀን ፡ ጢማቸውን ፡ ላጭተው ፡ ልብሳቸውንም ፡ ቀድደው ፡ ገላቸውንም ፡ ነጭተው ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡ የእህል ፡ ቍርባንና ፡ ዕጣን ፡ በእጃቸው ፡ እየያዙ ፥ ሰማንያ ፡ ሰዎች ፡ ከሴኬምና ፡ ከሴሎ ፡ ከሰማርያም ፡ መጡ ። ፮ የናታንያም ፡ ልጅ ፡ እስማኤል ፡ ከምጽጳ ፡ ወጥቶ ፡ እያለቀሰ ፡ ሊገናኛቸው ፡ ሄደ ፤ በተገናኛቸውም ፡ ጊዜ ፡— ወደ ፡ አኪቃም ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ጎዶልያስ ፡ ኑ ፡ አላቸው ። ፯ ወደ ፡ ከተማም ፡ መካከል ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ የናታንያ ፡ ልጅ ፡ እስማኤል ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩ ፡ ሰዎች ፡ ገደሉአቸው ፥ በጕድጓድም ፡ ፰ መካከል ፡ ጣሉአቸው ። በመካከላቸውም ፡ እስማኤልን ፡— በሜዳ ፡ የተሸሸገ ፡ ስንዴና ፡ ገብስ ፡ ዘይትና ፡ ማርም ፡ አለንና ፡ አትግደለን ፡ የሚሉት ፡ አሥር ፡ ሰዎች ፡ ተገኙ ። እርሱም ፡ ተዋቸው ፥ ከወንድሞቻቸውም ፡ ጋር ፡ አልገደላቸ ፱ ውም ። እስማኤልም ፡ ከጎዶልያስ ፡ ጋር ፡ የገደላቸውን ፡ የሰዎች ፡ ሬሳ ፡ ሁሉ ፡ የጣለበት ፡ ጕድጓድ ፡ ንጉሡ ፡ አሳ ፡ የእስራኤልን ፡ ንጉሥ ፡ ባኦስን ፡ ስለ ፡ ፈራ ፡ የሠራው ፡ ጕድጓድ ፡ ነበረ ፤ የናታንያም ፡ ልጅ ፡ እስማኤል ፡ የገደላቸውን ፡ ፲ ሞላበት ። እስማኤልም ፡ በምጽጳ ፡ የነበረውን ፡ የሕዝቡን ፡ ቅሬታ ፡ ሁሉ ፥ የንጉሡን ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡ ለአኪቃም ፡ ልጅ ፡ ለጎዶልያስ ፡ የሰጠውን ፡ በምጽጳ ፡ የቀሩትን ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ማረካቸው ፤ የናታንያም ፡ ልጅ ፡ እስማኤል ፡ ማርኮ ፡ ወደ ፡ አሞን ፡ ልጆች ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ ተነሣ ።

፲፩ የቃሬያም ፡ ልጅ ፡ ዮሐናን ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩ ፡ የጭፍራ ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ የናታንያ ፡ ልጅ ፡ እስማኤል ፡ ያደረገውን ፡ ክፋት ፡ ሁሉ ፡ ፲፪ በሰሙ ፡ ጊዜ ፥ ሰዎቹን ፡ ሁሉ ፡ ይዘው ፡ ከናታንያ ፡ ልጅ ፡ ከእስማኤል ፡ ጋር ፡ ሊዋጉ ፡ ሄዱ ፥ በገባዖንም ፡ ባለው ፡ በታላቁ ፡ ውኃ ፡ አጠገብ ፡ ፲፫ አገኙት ። ከእስማኤልም ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ የቃሬያን ፡ ልጅ ፡ ዮሐናንን ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩትን ፡ የጭፍራ ፡ አለቆችን ፡ ፲፬ ሁሉ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ አላቸው ። እስማኤልም ፡ ከምጽጳ ፡ የማረካቸው ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ዘወር ፡ ብለው ፡ ተመለሱ ፥ ወደ ፡ ቃሬያም ፡ ፲፭ ልጅ ፡ ወደ ፡ ዮሐናን ፡ ሄዱ ። የናታንያ ፡ ልጅ ፡ እስማኤል ፡ ግን ፡ ከስምንት ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ከዮሐናን ፡ አመለጠ ፡ ወደ ፡ አሞንም ፡ ልጆች ፡ ሄደ ።

፲፮ የቃሬያም ፡ ልጅ ፡ ዮሐናን ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ የጭፍራ ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ የአኪቃምን ፡ ልጅ ፡ ጎዶልያስን ፡ በምጽጳ ፡ ከገደለው ፡ በኋላ ፡ ከናታንያ ፡ ልጅ ፡ ከእስማኤል ፡ ያስመለሱአቸውን ፡ የሕዝቡን ፡ ቅሬታ ፡ ሁሉ ፥ ከገባዖን ፡ ያስመለሱአቸውን ፡ ሰልፈኞች ፥ ሴቶችንም ፥ ልጆችንም ፥ ጃንደረቦችንም ፥ ወሰዱ ፤ ፲፯ ተነሥተውም ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ በቤተ ፡ ልሔም ፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡ በጌሮት ፡ ከመዓም ፡ ተቀመጡ ፤ ፲፰ እስማኤል ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ በአገሩ ፡ ላይ ፡ የሾመውን ፡ የአኪቃምን ፡ ልጅ ፡ ጎዶልያስን ፡ ስለ ፡ ገደለው ፡ ከለዳውያንን ፡ ፈርተዋልና ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፪ ።

፩ የጭፍራ ፡ አለቆችም ፡ ሁሉ ፡ የቃሬያም ፡ ልጅ ፡ ዮሐናን ፡ የሆሻያም ፡ ልጅ ፡ ያእዛንያ ፡ ሕዝብም ፡ ሁሉ ፡ ከታናሹ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ድረስ ፡ ቀረቡ ፥ ፪ ነቢዩንም ፡ ኤርምያስን ፡— ፫ ዓይኖችህ ፡ እንዳዩን ፡ ከብዙ ፡ ጥቂት ፡ ቀርተናልና ፡ ልመናችን ፥ እባክህ ፥ በፊትህ ፡ ትድረስ ፤ አምላክህም ፡ እግዚአብሔር ፡ የምንሄድበትን ፡ መንገድና ፡ የምናደርገውን ፡ ነገር ፡ ያሳየን ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ እኛ ፥ ስለዚህ ፡ ቅሬታ ፡ ሁሉ ፥ ወደ ፡ አምላክህ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸልይ ፡ አሉት ። ፬ ነቢዩም ፡ ኤርምያስ ፡— ሰምቻችኋለሁ ፤ እነሆ ፥ እንደ ፡ ቃላችሁ ፡ ወደ ፡ አምላካችሁ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እጸልያለሁ ፤ እግዚአብሔርም ፡ የሚመልስላችሁን ፡ ሁሉ ፡ እነግራችኋለሁ ፥ ከእናንተም ፡ ምንም ፡ አልሸሽግም ፡ አላቸው ። ፭ ኤርምያስንም ፡— አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በአንተ ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ የላከውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ባናደርግ ፥ እግዚአብሔር ፡ በመካከላችን ፡ እውነተኛና ፡ ታማኝ ፡ ምስክር ፡ ይሁን ። ፮ የአምላካችንን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ በመስማታችን ፡ መልካም ፡ እንዲሆንልን ፥ መልካም ፡ ወይም ፡ ክፉ ፡ ቢሆን ፥ አንተን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ የምንልክህ ፡ የአምላካችንን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ እንሰማለን ፡ አሉት ።

፯ ከአሥር ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ መጣ ። ፰ የቃሬያንም ፡ ልጅ ፡ ዮሐናንን ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩትን ፡ የጭፍራ ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ከታናሹ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ድረስ ፡ ሕዝቡንም ፡ ሁሉ ፡ ጠራ ፥ ፱ እንዲህም ፡ አላቸው ፡— ጸሎታችሁን ፡ በፊቱ ፡ አቀርብ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ የላካችሁኝ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ፲ ስላደረግሁባችሁ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ተጸጽቻለሁና ፡ በዚህች ፡ ምድር ፡ ብትቀመጡ ፡ እሠራችኋለሁ ፡ እንጂ ፡ አላፈርሳችሁም ፥ እተክላችኋለሁ ፡ እንጂ ፡ አልነቅላችሁም ። ፲፩ ከምትፈሩት ፡ ከባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ አትፍሩ ፤ አድናችሁ ፡ ዘንድ ፡ ከእጁም ፡ አስጥላችሁ ፡ ዘንድ ፡

እኔ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ነኝና ፡ አትፍሩ ፥ ይላል ፡
፲፪ እግዚአብሔር ። እርሱ ፡ እንዲምራችሁ ፡ ወደ ፡
አገራችሁም ፡ እንዲመልሳችሁ ፡ እኔ ፡ እምራች
፲፫ ኋለሁ ። እናንተ ፡ ግን ፡— በዚህች ፡ ምድር ፡
አንቀመጥም ፡ ብትሉ ፡ የአምላካችሁንም ፡ የእ
፲፬ ግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ባትሰሙ ፥ እናንተም ፡—
አይደለም ፤ ሰልፍ ፡ ወደማናይበት ፡ የመለከ
ትም ፡ ድምፅ ፡ ወደማንሰማበት ፡ ወደማንራብ
ባትም ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ምድር ፡ እንሄዳለን ፡
፲፭ በዚያም ፡ እንቀመጣለን ፡ ብትሉ ፥ እናንተ ፡
የይሁዳ ፡ ቅሬታ ፡ ሆይ ፥ አሁን ፡ እንግዲህ ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስሙ ፤ የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— ወደ ፡ ግብጽ ፡ ትገቡ ፡ ዘንድ ፡ በዚ
ያም ፡ ትቀመጡ ፡ ዘንድ ፡ ፊታችሁን ፡ ብታቀኑ ፥
፲፮ የምትፈሩት ፡ ሰይፍ ፡ በዚያ ፡ በግብጽ ፡ ምድር ፡
ያገኛችኋል ፥ ስለ ፡ እርሱም ፡ የምትደነግጡበት ፡
ራብ ፡ በዚያ ፡ በግብጽ ፡ ይደርስባችኋል ፥ በዚ
፲፯ ያም ፡ ትሞታላችሁ ። ወደ ፡ ግብጽም ፡ ይገቡ ፡
ዘንድ ፡ በዚያም ፡ ይቀመጡ ፡ ዘንድ ፡ ፊታ
ቸውን ፡ በሚያቀኑ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡
ይሆንባቸዋል ፤ በሰይፍና ፡ በራብ ፡ በቸነፈርም ፡
ይሞታሉ ፤ እኔም ፡ ከማመጣባቸው ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡
ማንም ፡ አይቀርም ፥ ማንም ፡ አያመልጥም ።
፲፰ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— ቍጣዬና ፡
መዓቴ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በሚኖሩ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡
ፈሰሰ ፥ እንዲሁ ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ በገባችሁ ፡
ጊዜ ፡ መዓቴ ፡ ይፈስስባችኋል ፤ እናንተም ፡ ለጥ
ላቻና ፡ ለመደነቂያ ፡ ለመረገሚያና ፡ ለመሰደ
ቢያ ፡ ትሆናላችሁ ፥ ይህንም ፡ ስፍራ ፡ ከእንግ
፲፱ ዲህ ፡ ወዲህ ፡ አታዩትም ። እናንተ ፡ የይሁዳ ፡
ቅሬታ ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔር ፡— ወደ ፡ ግብጽ ፡
አትግቡ ፡ ብሎ ፡ ተናግሮባችኋልና ፡ ዛሬ ፡ እን
፳ ዳስጠነቀቅኋችሁ ፡ በእርግጥ ፡ እወቁ ። እና
ንተ ፡— ስለ ፡ እኛ ፡ ወደ ፡ አምላካችን ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ጸልይ ፥ አምላካችንም ፡ እግዚ
አብሔር ፡ የሚናገርህን ፡ ሁሉ ፡ ንገረን ፡ እኛም ፡
እናደርገዋለን ፡ ብላችሁ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ወደ ፡ አምላካችሁ ፡ ልካችሁኝ ፡ ነበርና ፡ ራሳ
፳፩ ችሁን ፡ አታልላችኋል ። እኔም ፡ ዛሬ ፡ ነግሬአ
ችኋለሁ ፥ ወደ ፡ እናንተም ፡ በላከኝ ፡ ነገር ፡
ሁሉ ፡ የአምላካችሁን ፡ የእግዚአብሔርን ፡
፳፪ ቃል ፡ አልሰማችሁም ። አሁንም ፡ ሄዳችሁ ፡
እንድትቀመጡ ፡ በወደዳችሁበት ፡ ስፍራ ፡ በሰ
ይፍና ፡ በራብ ፡ በቸነፈርም ፡ እንድትሞቱ ፡ በእ
ርግጥ ፡ እወቁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፫ ።

፩ የአምላካቸውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
ሁሉ ፥ ለእነርሱ ፡ አምላካቸው ፡ እግዚአብሔር ፡
የላከውን ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፥ ኤርምያስ ፡
ለሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ መናገርን ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፥
፪ የሆሻያ ፡ ልጅ ፡ ዓዛርያስ ፡ የቃሬያም ፡ ልጅ ፡
ዮሐናን ፡ ትዕቢተኞችም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ኤር
ምያስን ፡— ሐሰት ፡ ተናግረሃል ፤ አምላካችን ፡
እግዚአብሔር ፡— በዚያ ፡ ትቀመጡ ፡ ዘንድ ፡
፫ ወደ ፡ ግብጽ ፡ አትግቡ ፡ ብሎ ፡ አልላከህም ፤ ነገር ፡
ግን ፡ ከለዳውያን ፡ እንዲገድሉን ፡ ወደ ፡ ባቢ
ሎንም ፡ እንዲማርኩን ፡ በእጃቸው ፡ አሳልፈህ ፡
ትሰጠን ፡ ዘንድ ፡ የኔርያ ፡ ልጅ ፡ ባሮክ ፡ በላያ
፬ ችን ፡ ላይ ፡ አነሣሥቶሃል ፡ አሉት ። የቃሬያም ፡
ልጅ ፡ ዮሐናን ፡ የጭፍራ ፡ አለቆችም ፡ ሁሉ ፡
ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በይሁዳ ፡ ምድር ፡ ይቀመጡ ፡
ዘንድ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አልሰሙም ።
፭ የቃሬያም ፡ ልጅ ፡ ዮሐናን ፡ የጭፍራ ፡ አለቆ
ችም ፡ ሁሉ ፡ በይሁዳ ፡ ምድር ፡ ለመቀመጥ ፡
ከተሰደዱባቸው ፡ ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ የተመለሱ
፮ ትን ፡ የይሁዳን ፡ ቅሬታ ፡ ሁሉ ፥ ወንዶችንና ፡
ሴቶችን ፡ ልጆችንም ፡ የንጉሡንም ፡ ሴቶች ፡
ልጆች ፥ የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡ ከሳ
ፋን ፡ ልጅ ፡ ከአኪቃም ፡ ልጅ ፡ ከጎዶልያስ ፡ ጋር ፡
የተዋቸውን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፥ ነቢዩንም ፡ ኤር
ምያስን ፡ የኔርያንም ፡ ልጅ ፡ ባሮክን ፡ ወሰዱ ፤
፯ የእግዚአብሔርንም ፡ ቃል ፡ አልሰሙምና ፡ ወደ ፡
ግብጽ ፡ ምድር ፡ ገቡ ፥ እስከ ፡ ጣፍናስ ፡ ድረስ ፡
መጡ ።

፰ በጣፍናስም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡
፱ ኤርምያስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ታላላቆ
ችን ፡ ድንጋዮች ፡ በእጅህ ፡ ውሰድ ፥ የይሁ
ዳም ፡ ሰዎች ፡ እያዩ ፡ በጣፍናስ ፡ ባለው ፡ በፈር
፲ ዖን ፡ ቤት ፡ ደጅ ፡ መግቢያ ፡ ሸሸጋቸው ፤ እንዲ
ህም ፡ በላቸው ፡— የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠ
ራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
እነሆ ፥ ልኬ ፡ ባሪያዬን ፡ የባቢሎንን ፡ ንጉሥ ፡
ናቡከደነፆርን ፡ አመጣለሁ ፥ ዙፋኑንም ፡ እኔ ፡
በሸሸግኋቸው ፡ በእነዚህ ፡ ድንጋዮች ፡ ላይ ፡
አኖራለሁ ፤ እርሱም ፡ ማለፊያውን ፡ ድንኳኑን ፡
፲፩ በላያቸው ፡ ይዘረጋል ። መጥቶም ፡ የግብጽን ፡
ምድር ፡ ይመታል ፥ ለሞትም ፡ የሚሆነውን ፡
ለሞት ፥ ለምርኮም ፡ የሚሆነውን ፡ ለምርኮ ፥
ለሰይፍም ፡ የሚሆነውን ፡ ለሰይፍ ፡ አሳልፎ ፡
፲፪ ይሰጣል ። በግብጽም ፡ አማልክት ፡ ቤቶች ፡
እሳትን ፡ ያነድዳል ፡ ያቃጥላቸውማል ፡ ይማር
ካቸውማል ፤ እረኛም ፡ ደበሎውን ፡ እንደሚደ
ርብ ፡ እንዲሁ ፡ የግብጽን ፡ አገር ፡ ይደርባል ፤
፲፫ ከዚያም ፡ በሰላም ፡ ይወጣል ። በግብጽም ፡
ምድር ፡ ያለውን ፡ የሄልዮቱን ፡ ከተማ ፡ ሐው
ልቶች ፡ ይሰብራል ፥ የግብጽንም ፡ አማልክት ፡
ቤቶች ፡ በእሳት ፡ ያቃጥላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፬ ።

፩ በግብጽ ፡ ምድር ፡ በሚግዶልና ፡ በጣፍናስ ፡
በሜምፎስም ፡ በጳትሮስም ፡ አገር ፡ ስለ ፡ ተቀ
መጡ ፡ አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡
፪ የመጣ ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፡— በኢየሩሳሌምና ፡ በይሁዳ ፡ ከተ

ሞች ፡ ሁሉ ፡ ያመጣሁትን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡
አይታችኋል ፤ እነሆ ፥ ዛሬ ፡ ባድማ ፡ ሆነዋል ፥
፫፤ የሚቀመጥባቸውም ፡ የለም ። ይህም ፡ የሆ
ነው ፡ ያስቈጡኝ ፡ ዘንድ ፡ ስላደረጉት ፡ ክፋት ፥
ለማያውቁአቸውም ፡ ለሌሎች ፡ አማልክት ፡
ያጥኑ ፡ ዘንድ ፡ ያመልኩአቸውም ፡ ዘንድ ፡ ስለ
፬፤ ሄዱ ፡ ነው ። በማለዳም ፡ ተነሥቼ ፡ ባሪያዎቼን ፡
ነቢያትን ፡ ሁሉ ፡ ሰደድሁባችሁና ፦ እንደ
ዚህ ፡ እንደ ፡ ጠላሁት ፡ ያለ ፡ ርኩስ ፡ ነገር ፡ አታ
፭፤ ድርጉ ፡ አልኋችሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ አልሰሙም ፡
ከክፋታቸውም ፡ ተመልሰው ፡ ለሌሎች ፡ አማ
ልክት ፡ እንዳያጥኑ ፡ ጆሮአቸውን ፡ አላዘነበ
፮፤ ሉም ። ስለዚህ ፡ መዓቴና ፡ ቍጣዬ ፡ ፈሰሱ ፥
በይሁዳም ፡ ከተሞችና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አደ
ባባይ ፡ ነደዱ ፤ ዛሬም ፡ እንደ ፡ ሆነው ፡ ፈረሱ ፡
፯፤ ባድማም ፡ ሆኑ ። አሁንም ፡ የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፦ ከይሁዳ ፡ ወገን ፡ ቅሬታ ፡ እንዳይ
ቀርላችሁ ፥ ወንድንና ፡ ሴትን ፥ ብላቴናንና ፡
ሕፃንን ፡ ከመካከላችሁ ፡ ታጠፉ ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡
ታላቅ ፡ ክፋት ፡ በራሳችሁ ፡ ላይ ፡ ለምን ፡ ታደ
፰፤ ርጋላችሁ ? ሰውነታችሁንም ፡ ታጠፉ ፡ ዘንድ ፡
በምድርም ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ መረገ
ሚያና ፡ መሰደቢያ ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ፥ ለመቀ
መጥ ፡ በገባችሁበት ፡ በግብጽ ፡ ምድር ፡ ለሌ
ሎች ፡ አማልክት ፡ በማጠናችሁ ፡ በእጃችሁ ፡
፱፤ ሥራ ፡ ለምን ፡ ታስቈጡኛላችሁ ? በውኑ ፡ በይ
ሁዳ ፡ ምድርና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አደባባይ ፡
ያደረጉትን ፡ የአባቶቻችሁን ፡ ክፋት ፥ የይሁ
ዳንም ፡ ነገሥታት ፡ ክፋት ፥ የሚስቶቻቸው
ንም ፡ ክፋት ፥ የእናንተንም ፡ ክፋት ፥ የሚ
ስቶቻችሁንም ፡ ክፋት ፡ ረስታችሁታልን ?
፲፤ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ አልተዋረዱም ፡ አልፈሩ
ምም ፥ በእናንተና ፡ በአባቶቻችሁም ፡ ፊት ፡
በኖርሁት ፡ ሕጌና ፡ ሥርዓቴ ፡ አልሄዱም ።
፲፩፤ ስለዚህም ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እነሆ ፥
ይሁዳን ፡ ሁሉ ፡ አጠፋ ፡ ዘንድ ፡ ፊቴን ፡ ለክ
፲፪፤ ፋት ፡ በላያችሁ ፡ አደርጋለሁ ። ወደ ፡ ግብጽም ፡
ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ በዚያም ፡ ይቀመጡ ፡ ዘንድ ፡
ፊታቸውን ፡ ያቀኑትን ፡ የይሁዳን ፡ ቅሬታ ፡ እወ
ስዳለሁ ፥ ሁሉም ፡ ይጠፋሉ ፥ በግብጽም ፡
ምድር ፡ ይወድቃሉ ፤ በሰይፍና ፡ በራብ ፡ ይጠ
ፋሉ ፤ ከታናሹም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡
ድረስ ፡ በሰይፍና ፡ በራብ ፡ ይሞታሉ ፤ ለጥላ
ቻና ፡ ለመደነቂያ ፡ ለመረገሚያና ፡ ለመሰደቢያ ፡
፲፫፤ ይሆናሉ ። ኢየሩሳሌምንም ፡ እንደ ፡ ቀጣሁ ፥
እንዲሁ ፡ በግብጽ ፡ ምድር ፡ የሚኖሩትን ፡ በሰ
፲፬፤ ይፍና ፡ በራብ ፡ በቸነፈርም ፡ እቀጣለሁ ። በዚያ ፡
ለመቀመጥ ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ምድር ፡ ከሄዱ ፥
ወደ ፡ ይሁዳ ፡ አገር ፡ ተመልሰው ፡ በዚያ ፡ ይቀ
መጡ ፡ ዘንድ ፡ ከሚወድዱ ፡ ከይሁዳ ፡ ቅሬታ ፡
ወገን ፡ የሚያመልጥና ፡ የሚቀር ፡ ወደዚያም ፡
የሚመለስ ፡ የለም ፤ ከሚያመልጥም ፡ በቀር ፡
ማንም ፡ አይመለስም ።

፲፭፤ ሚስቶቻቸውም ፡ ለሌሎች ፡ አማልክት ፡ ማጠ
ናቸውን ፡ ያወቁ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በዚያም ፡
የቆሙ ፡ ሴቶች ፡ ሁሉ ፥ በግብጽ ፡ ምድር ፡ በጳ
ትሮስ ፡ የተቀመጡ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፥ ታላቅ ፡
ጉባኤ ፡ ሆነው ፡ ለኤርምያስ ፡ መለሱለት ፡ እን
፲፮፤ ዲህም ፡ አሉ ፦ አንተ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡
፲፯፤ የነገርኸንን ፡ ቃል ፡ አንሰማህም ። ነገር ፡ ግን ፡
እኛና ፡ አባቶቻችን ፡ ነገሥታቶቻችንም ፡ አለ
ቆቻችንም ፡ በይሁዳ ፡ ከተሞች ፡ በኢየሩሳሌም ፡
አደባባይ ፡ እናደርገው ፡ እንደ ፡ ነበረ ፥ ለሰ
ማይ ፡ ንግሥት ፡ እናጥን ፡ ዘንድ ፡ የመጠጥንም ፡
ቍርባን ፡ እናፈስስላት ፡ ዘንድ ፡ ከአፋችን ፡ የወ
ጣውን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ በእርግጥ ፡ እናደርጋለን ፤
በዚያን ፡ ጊዜም ፡ እንጀራ ፡ እንጠግብ ፡ ነበር ፥
መልካምም ፡ ይሆንልን ፡ ክፉም ፡ አናይም ፡
፲፰፤ ነበር ። ለሰማይ ፡ ንግሥት ፡ ማጠንን ፡ ለእርስ
ዋም ፡ የመጠጥን ፡ ቍርባን ፡ ማፍሰስን ፡ ከተ
ውን ፡ ወዲህ ፡ ግን ፥ እኛ ፡ በሁሉ ፡ ነገር ፡ ተቸ
፲፱፤ ግረናል ፥ በሰይፍና ፡ በራብ ፡ አልቀናል ። እኛስ ፡
ለሰማይ ፡ ንግሥት ፡ ባጠንንላት ፡ የመጠጥንም ፡
ቍርባን ፡ በፈሰስንላት ፡ ጊዜ ፥ በውኑ ፡ ያለ ፡
ባሎቻችን ፡ ምስልዋን ፡ ለማበጀት ፡ እንጐቻ ፡
አድርገንላት ፡ ኖሮአልን ? የመጠጥንም ፡ ቍር
ባን ፡ አፍስሰንላት ፡ ኖሮአልን ?

፳፤ ኤርምያስም ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ለመለሱለት ፡
ሕዝብ ፡ ሁሉ ፥ ለወንዶቹና ፡ ለሴቶቹ ፡ ለሕዝ
ቡም ፡ ሁሉ ፥ መለሰላቸው ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦
፳፩፤ እናንተና ፡ አባቶቻችሁ ፡ ነገሥታቶቻችሁም ፡
አለቆቻችሁም ፡ የምድርም ፡ ሕዝብ ፡ በይሁዳ ፡
ከተሞችና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አደባባይ ፡ ያጠና
ችሁትን ፡ ዕጣን ፡ እግዚአብሔር ፡ ያሰበው ፡ በል
፳፪፤ ቡም ፡ ያኖረው ፡ አይደለምን ? እግዚአብሔርም ፡
ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ የሥራችሁን ፡ ክፋትና ፡
ያደረጋችሁትን ፡ ርኵሰት ፡ ይታገሥ ፡ ዘንድ ፡
አልቻለም ፤ ስለዚህ ፡ ምድራችሁ ፡ ባድማ ፡ መደ
ነቂያም ፡ መረገሚያም ፡ ሆናለች ፡ ዛሬም ፡ እንደ ፡
፳፫፤ ሆነ ፡ የሚኖርባት ፡ የለም ። ስላጠናችሁ ፥ በእ
ግዚአብሔርም ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ በደላችሁ ፥ የእግዚ
አብሔርንም ፡ ቃል ፡ ስላልሰማችሁ ፥ በሕጉና ፡
በሥርዓቱም ፡ በምስክሩም ፡ ስላልሄዳችሁ ፥ ስለ
ዚህ ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይህች ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አግ
ኝታችኋለች ።

፳፬፤ ኤርምያስም ፡ ለሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ለሴቶቹም ፡
ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ በግብጽ ፡ ምድር ፡ የም
ትኖሩ ፡ ይሁዳ ፡ ሁሉ ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
፳፭፤ ስሙ ። የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እናንተና ፡
ሚስቶቻችሁ ፡ በአፋችሁ ፦ ለሰማይ ፡ ንግ
ሥት ፡ እናጥን ፡ ዘንድ ፡ የመጠጥንም ፡ ቍርባን ፡
እናፈስስላት ፡ ዘንድ ፡ የተሳልነውን ፡ ስእለታች
ንን ፡ በእርግጥ ፡ እንፈጽማለን ፡ አላችሁ ፡ በእጃች
ሁም ፡ አደረጋችሁት ፤ እንግዲህ ፡ ስእለታች
፳፮፤ ሁን ፡ አጽኑ ፡ ስእለታችሁንም ፡ ፈጽሙ ። እና

ንተ ፡ በግብጽ ፡ ምድር ፡ የምትኖሩ ፡ ይሁዳ ፡
ሁሉ ÷ ስለዚህ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስሙ ፤
በግብጽ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ በሚኖር ፡ በይሁዳ ፡
ሰው ፡ ሁሉ ፡ አፍ ፡ ስሜ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡—
ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! ተብሎ ፡ እንዳይጠራ ÷
እነሆ ÷ በታላቅ ፡ ስሜ ፡ ምያለሁ ÷ ይላል ፡ እግ
፳፯ ዚአብሔር ። እነሆ ÷ ለመልካም ፡ ሳይሆን ፡ ለክ
ፋት ፡ እተጋባቸዋለሁ ፤ በግብጽም ፡ ምድር ፡
ያሉት ፡ የይሁዳ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ እስኪጠፉ ፡
፳፰ ድረስ ፡ በሰይፍና ፡ በራብ ፡ ያልቃሉ ። ከሰይፍም ፡
የሚያመልጡ ፡ ጥቂት ፡ ሰዎች ፡ ሆነው ፡ ከግ
ብጽ ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ምድር ፡ ይመለሳሉ ፤
ሊቀመጡም ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ምድር ፡ የገቡት ፡
የይሁዳ ፡ ቅሬታ ፡ ሁሉ ፡ ከእኔ ፡ ወይም ፡ ከእነ
ርሱ ፡ የማናችን ፡ ቃል ፡ እንዲጸና ፡ ያውቃሉ ።
፳፱ ቃሌም ፡ በላያችሁ ፡ ለክፋት ፡ እንዲጸና ፡ ታውቁ ፡
ዘንድ ፡ በዚህች ፡ ስፍራ ፡ እንድቀጣችሁ ፡ ምል
ክታችሁ ፡ ይህ ፡ ነው ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
፴ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የይሁዳን ፡
ንጉሥ ፡ ሴዴቅያስን ፡ ጠላቱ ፡ ለሆነው ፡ ነፍሱ
ንም ፡ ለፈለገው ፡ ለባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ለናቡከ
ደነፆር ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ እንደ ፡ ሰጠሁት ÷ እን
ዲሁ ÷ እነሆ ÷ የግብጽን ፡ ንጉሥ ፡ ፈርዖን ፡
ሖፍራን ፡ ለጠላቶቹ ፡ ነፍሱንም ፡ ለሚፈልጉ ፡
እጅ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጠዋለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፭ ።

፩ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ በኢ
ዮአቄም ፡ በአራተኛው ፡ ዓመት ፡ የኔርያ ፡ ልጅ ፡
ባሮክ ፡ እነዚህን ፡ ቃሎች ፡ ከኤርምያስ ፡ አፍ ፡ በመ
ጽሐፍ ፡ በጻፋቸው ፡ ጊዜ ÷ ነቢዩ ፡ ኤርምያስ ፡
፪ የተናገረው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። ባሮክ ፡ ሆይ ÷
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
፫ ይልሃል ፡— አንተ ፡— እግዚአብሔር ፡ በሕመሜ ፡
ላይ ፡ ኀዘንን ፡ ጨምሮብኛልና ፡ ወዮልኝ ! በል
ቅሶዬ ፡ ጩኸት ፡ ደክሜአለሁ ÷ ዕረፍትንም ፡
፬ አላገኘሁም ፡ ብለሃል ። እንዲህ ፡ በለው ፡— እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ የሠራ
ሁትን ፡ አፈርሳለሁ ÷ የተከልሁትንም ፡ እነቅላ
፭ ለሁ ፤ ይኸውም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ነው ። ለራ
ስህ ፡ ታላቅን ፡ ነገር ፡ ትፈልጋለህን ? በሥጋ ፡
ለበሽ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ÷ እነሆ ÷ ክፉ ፡ ነገርን ፡ አመ
ጣለሁና ፡ አትፈልገው ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤
ነገር ፡ ግን ፡ በሄድህበት ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ ነፍስ
ህን ፡ እንደ ፡ ምርኮ ፡ አድርጌ ፡ እሰጥሃለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፮ ።

፩ ስለ ፡ አሕዛብ ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡
የመጣው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ።
፪ ስለ ፡ ግብጽ ፤ በኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡
በከርከሚሽ ፡ ስለ ፡ ነበረው ÷ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡
በኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ በኢዮአቄም ፡ በአራተ
ኛው ፡ ዓመት ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነ
ፆር ፡ ስለ ፡ መታው ፡ ስለ ፡ ግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ስለ ፡
ፈርዖን ፡ ኒካው ፡ ሠራዊት ።
፫ ጋሻ ፡ ጦር ፡ አዘጋጁ ፡ ወደ ፡ ሰልፍም ፡ ቅረቡ ።
፬ ፈረሰኞች ፡ ሆይ ÷ ፈረሶችን ፡ ለጕሙና ፡ ውጡ ÷
ራስ ፡ ቍርንም ፡ ደፍታችሁ ፡ ቁሙ ፤ ጦርንም ፡
፭ ሰንግሉ ፡ ጥሩርንም ፡ ልበሱ ። ፈርተው ፡ ወደ ፡
ኋላ ፡ ሲመለሱ ÷ ኃያላኖቻቸውም ፡ ሲደበደቡ ፡
ወደ ፡ ኋላቸውም ፡ ሳይመለከቱ ፡ ፈጥነው ፡
ሲሸሹ ፡ ለምን ፡ አየሁ ? በዚህና ፡ በዚያ ፡ ድን
፮ ጋጤ ፡ አለ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፈጣኑ ፡
አያመልጥም ፡ ኃያሉም ፡ አይድንም ፤ በሰሜን ፡
በኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ በኩል ፡ ተሰናክለው ፡
፯ ወደቁ ። ይህ ፡ እንደ ፡ ግብጽ ፡ ወንዝ ፡ የሚ
ነሣ ÷ ውኃውም ፡ እንደ ፡ ወንዝ ፡ የሚናወጥ ፡
፰ ማን ፡ ነው ? ግብጽ ፡ እንደ ፡ ግብጽ ፡ ወንዝ ፡
ይነሣል ፡ ውኃውም ፡ እንደ ፡ ወንዙ ፡ ይናወ
ጣል ፤ እርሱም ፡— እነሣለሁ ፡ ምድርንም ፡
ሁሉ ፡ እከድናለሁ ፤ ከተሞችንና ፡ የሚኖሩባቸ
፱ ውን ፡ አጠፋለሁ ፡ ብሎአል ። ፈረሶች ፡ ሆይ ÷
ውጡ ፤ ሰረገሎችም ፡ ሆይ ÷ ንጐዱ ፤ ጋሻም ፡ የሚ
ያነግቡ ፡ የኢትዮጵያና ፡ የፉጥ ፡ ኃያላን ÷ ቀስት
ንም ፡ ይዘው ፡ የሚስቡ ፡ የሉድ ፡ ኃያላን ፡ ይውጡ ።
፲ ያ ፡ ቀን ፡ ጠላቶቹን ፡ የሚበቀልበት ፡ የሠራዊት ፡
ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ የበቀል ፡ ቀን ነው ፤ ሰይፍ ፡
በልቶ ፡ ይጠግባል ፡ በደማቸውም ፡ ይሰክራል ÷
ለሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በሰሜን ፡
ምድር ፡ በኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ መሥ
፲፩ ዋዕት ፡ አለውና ። ድንግሊቱ ፡ የግብጽ ፡ ልጅ ፡
ሆይ ÷ ወደ ፡ ገለዓድ ፡ ውጪ ፡ የሚቀባንም ፡
መድኃኒት ፡ ውሰጂ ፤ መድኃኒትን ፡ ያበዛሽው ፡
፲፪ በከንቱ ፡ ነው ፤ መዳን ፡ የለሽም ። ኃያሉ ፡ በኃ
ያሉ ፡ ላይ ፡ ተሰናክሎ ፡ ሁለቱ ፡ በአንድነት ፡
ወድቀዋልና ፡ አሕዛብ ፡ ጕስቍልናሽን ፡ ሰምተ
ዋል ÷ ልቅሶሽም ፡ ምድርን ፡ ሞልቶአታል ።
፲፫ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ እንዲመ
ጣና ፡ የግብጽን ፡ ምድር ፡ እንዲመታ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ለነቢዩ ፡ ለኤርምያስ ፡ የተናገረው ፡
ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ።
፲፬ በግብጽ ፡ ተናገሩ ÷ በሚግዶልም ፡ አሰሙ ÷
በሜምፎስና ፡ በጣፍናስ ፡ አሰሙ ፤ ሰይፍ ፡ በዙ
ሪያህ ፡ ያለውን ፡ በልቶአልና ፡— ተነሥ ፡ ተዘጋ
፲፭ ጅም ፡ በሉ ። ኃይለኞችህ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ተወ
ገዱ ? እግዚአብሔር ፡ ስላደከማቸው ፡ አልቆ
፲፮ ሙም ። ብዛታቸውም ፡ ተሰናከለ ÷ ሰውም ፡
አንዱ ፡ በአንዱ ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፤ እነርሱም ፡—
ተነሡ ÷ ከሚያስጨንቅ ፡ ሰይፍ ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ወገ
ናችን ፡ ወደ ፡ ተወለድንበት ፡ ምድር ፡ እንመለስ ፡
፲፯ አሉ ። በዚያም ፡ የግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ፈርዖንን ፡—
ሰዓቱን ፡ የሚያሳልፍ ፡ ጕረኛ ፡ ብለው ፡
፲፰ ጠሩት ። እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ በተራሮች ፡
መካከል ፡ እንዳለ ፡ እንደ ፡ ታቦር ÷ በባሕርም ፡
አጠገብ ፡ እንዳለ ፡ እንደ ፡ ቀርሜሎስ ÷ እንዲሁ ፡
በእውነት ፡ ይመጣል ÷ ይላል ፡ ስሙ ፡ የሠራ
ዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ የተባለው ፡ ንጉሥ ።
፲፱ አንቺ ፡ በግብጽ ፡ የምትቀመጪ ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷

ሚምፎስ ፡ ባድማ ፡ ትሆናለችና ፥ ትቃጠልማ
ለችና ፥ የሚቀመጥባትም ፡ አይገኝምና ፡ ለም
፳፩ ርከ ፡ የሚሆን ፡ ዕቃ ፡ አዘጋጂ ። ግብጽ ፡ የተዋ
በች ፡ ጊደር ፡ ናት ፤ ጥፋት ፡ ግን ፡ ይመጣል ፥
፳፩ ከሰሜን ፡ በኩል ፡ ይመጣበታል ። በእርስዋም ፡
ያሉ ፡ የተቀጠሩ ፡ ሠራተኞች ፡ እንደ ፡ ሰቡ ፡
ወይፈኖች ፡ ናቸው ፤ የጥፋታቸው ፡ ቀንና ፡
የመጐብኘታቸው ፡ ጊዜ ፡ መጥቶባቸዋልና ፡
ተመለሱ ፥ በአንድነትም ፡ ሸሹ ፥ አልቆሙ
፳፪ ምም ። ከሠራዊትም ፡ ጋር ፡ ይሄዳሉና ፡ ድምፅ ፡
እንደ ፡ እባብ ፡ ይተምማል ፤ እንደ ፡ እንጨት ፡
፳፫ ቈራጮችም ፡ በምሳር ፡ ይመጡባታል ። ይቈ
ጠሩ ፡ ዘንድ ፡ የማይቻሉትን ፡ የዱርዋን ፡ ዛፎች ፡
ይቈርጣሉ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ከአንበጣ ፡
ይልቅ ፡ በዝተዋልና ፡ ቍጥርም ፡ የላቸውምና ።
፳፬ የግብጽ ፡ ልጅ ፡ ታፍራለች ፤ በሰሜን ፡ ሕዝብ ፡
፳፭ እጅ ፡ አልፋ ፡ ትሰጣለች ። የእስራኤል ፡ አም
ላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እነሆ ፥ የኖእ ፡ አሞንን ፥ ፈርዖንንም ፥
ግብጽንም ፥ አማልክቶችዋንና ፡ ነገሥታቶች
ዋንም ፥ ፈርዖንና ፡ በእርሱም ፡ የሚታመኑትን ፡
፳፮ እቀጣለሁ ፤ ነፍሳቸውንም ፡ በሚፈልጉ ፡ ሰዎች ፡
እጅ ፥ በባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ በናቡከደነፆር ፡
እጅ ፥ በባሪያዎቹም ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣቸ
ዋለሁ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ቀድሞው ፡
ዘመን ፡ የሰው ፡ መኖሪያ ፡ ትሆናለች ፥ ይላል ፡
እግዚአብሔር ።

፳፯ ነገር ፡ ግን ፡ አንተ ፡ ባሪያዬ ፡ ያዕቆብ ፡ ሆይ ፥
አትፍራ ፥ አንተም ፡ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ አትደ
ንግጥ ፤ እነሆ ፥ አንተን ፡ ከሩቅ ፡ ዘርህንም ፡ ከተ
ማረከበት ፡ ምድር ፡ አድናለሁ ፤ ያዕቆብም ፡
ተመልሶ ፡ ያርፋል ፡ ተዘልሎም ፡ ይቀመጣል ፥
፳፰ ማንም ፡ አያስፈራውምም ። አንተ ፡ ባሪያዬ ፡
ያዕቆብ ፡ ሆይ ፥ እኔ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነኝና ፡
አትፍራ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ አንተንም ፡
ያሰደድሁባቸውን ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሜ ፡
አጠፋለሁና ፥ አንተን ፡ ግን ፡ ፈጽሜ ፡ አላጠፋ
ህም ፤ በመጠን ፡ እቀጣሃለሁ ፥ ያለ ፡ ቅጣትም ፡
አልተውህም ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፯ ።

፩ ፈርዖንም ፡ ጋዛን ፡ ሳይመታ ፡ ስለ ፡ ፍልስጥኤ
ማውያን ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ የመ
፪ ጣው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ፥ ውኃ ፡
ከሰሜን ፡ ይነሣል ፡ የሚያጥለቀልቅም ፡ ፈሳሽ ፡
ይሆናል ፤ በአገሪቱና ፡ በመላዋ ፡ ሁሉ ፥ በከተማ
ይቱና ፡ በሚኖሩባት ፡ ላይ ፡ ይጐርፋል ፤ ሰዎቹም ፡
ይጮኻሉ ፥ በምድርም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ያለቅ
፫ ሳሉ ። ከኃይለኞች ፡ ፈረሶች ፡ ከኮቴያቸው ፡ መጠ
ብጠብ ፡ ድምፅ ፥ ከሰረገሎቹም ፡ መሽከርከር ፥
ከመንኰራኵሮቹም ፡ መትመም ፡ የተነሣ ፡ አባ
ቶች ፡ በእጃቸው ፡ ድካም ፡ ምክንያት ፡ ፊታቸ
ውን ፡ መልሰው ፡ ወደ ፡ ልጆቻቸው ፡ አይመለ

፬ ከቱም ። ይህም ፡ የሚሆነው ፡ ፍልስጥኤማው
ያንን ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ የቀሩትንም ፡ ረዳ
ቶች ፡ ሁሉ ፡ ከጢሮስና ፡ ከሲዶና ፡ ይቈርጥ ፡
ዘንድ ፡ ስለሚመጣው ፡ ቀን ፡ ነው ፤ እግዚአ
ብሔር ፡ ፍልስጥኤማውያንና ፡ የከፍቶርን ፡
፭ ደሴት ፡ ቅሬታ ፡ ያጠፋልና ። ቡሀነት ፡ በጋዛ ፡ ላይ ፡
መጥቶአል ፤ አስቀሎና ፡ ጠፋች ፤ የዔናቅ ፡ ቅሬ
ታዎች ፡ ሆይ ! እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ገላችሁን ፡
፮ ትነጫላችሁ ? አንተ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰይፍ ፡
ሆይ ፥ ዝም ፡ የማትለው ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ?
ወደ ፡ ሰገባህ ፡ ግባ ፡ ጸጥ ፡ ብለህም ፡ ዕረፍ ።
፯ እግዚአብሔር ፡ በአስቀሎናና ፡ በባሕር ፡ዳር ፡
ላይ ፡ ትእዛዝ ፡ ሰጥቶአልና ፥ በዚያም ፡ አዘጋጅ
ቶታልና ፡ እንዴት ፡ ዝም ፡ ትላለህ ?

## ምዕራፍ ፡ ፵፰ ።

፩ ስለ ፡ ሞዓብ ፤ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራ
ዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ናባው ፡ ጠፍታለችና ፡ ወዮላት ! ቂርያታ
ይም ፡ አፍራለች ፡ ተይዛማለች ፤ ሚሥጋብ ፡
፪ አፍራለች ፡ ደንግጣማለች ። ከእንግዲህ ፡
ወዲህ ፡ የሞዓብ ፡ ትምክሕት ፡ የለም ፤ በሐሴ
ቦን ፡ ላይ ፡— ኑ ፡ ሕዝብ ፡ እንዳትሆን ፡ እናጥ
ፋት ፡ ብለው ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አስበውባታል ።
መድሜን ፡ ሆይ ፥ አንቺ ፡ ደግሞ ፡ ትጠፊአለሽ ፡
፫ ሰይፍም ፡ ያሳድድሻል ። መፍረስና ፡ ታላቅ ፡
ጥፋት ፡ የሚል ፡ የጩኸት ፡ ቃል ፡ ከሖሮናይም ፡
፬ ተሰማ ። ሞዓብ ፡ ጠፍታለች ፥ ልጆችዋም ፡
፭ ጩኸትን ፡ አሰምተዋል ። በሉሒት ፡ ዓቀበት ፡
ልቅሶ ፡ እያለቀሱ ፡ ይወጣሉና ፥ በሖሮናይምም ፡
ቍልቍለት ፡ የጥፋትንና ፡ የመባባትን ፡ ጩኸት ፡
፮ ሰምተዋል ። ሽሽታችሁ ፡ ራሳችሁን ፡ አድኑ ፤
፯ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንዳለ ፡ ቍጥቋጦ ፡ ሁኑ ። በሥ
ራሽና ፡ በመዝገብሽ ፡ ታምነሻልና ፡ አንቺ ፡
ደግሞ ፡ ትያዢያለሽ ፤ ካሞሽም ፡ ከካህናቱና ፡
፰ ከአለቆቹ ፡ ጋር ፡ በአንድነት ፡ ይማረካል ። እግ
ዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፥ አጥፊ ፡ ወደ ፡
ከተማ ፡ ሁሉ ፡ ይመጣል ፡ አንዲትም ፡ ከተማ ፡
አትድንም ፤ ሸለቆውም ፡ ይጠፋል ፡ ሜዳውም ፡
፱ ይበላሻል ። በርራ ፡ እንድትወጣ ፡ ለሞዓብ ፡
ክንፍ ፡ ስጡአት ! ከተሞችዋም ፡ ባድማና ፡
፲ ወና ፡ ይሆናሉ ። የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡
በቸልታ ፡ የሚያደርግ ፡ ርጉም ፡ ይሁን ፥ ሰይ
ፉንም ፡ ከደም ፡ የሚከለክል ፡ ርጉም ፡ ይሁን ።
፲፩ ሞዓብ ፡ ከታናሽነቱ ፡ ጀምሮ ፡ ቅምጥል ፡
ነበረ ፥ በአምቡላውም ፡ ላይ ፡ ዐርፎአል ፥ ከዕ
ቃውም ፡ ወደ ፡ ዕቃ ፡ አልተገላበጠም ፥ ወደ ፡
ምርኮም ፡ አልሄደም ፤ ስለዚህ ፡ ቃናው ፡ በእ
ርሱ ፡ ውስጥ ፡ ቀርቶአል ፥ መዓዛውም ፡ አልተ
፲፪ ለወጠም ። ስለዚህ ፥ እነሆ ፥ የሚያገላብጡትን ፡
የምልክበት ፡ ዘመን ፡ ይመጣል ፥ ይላል ፡ እግ
ዚአብሔር ፥ እነርሱም ፡ ያገላብጡታል ፤ ጋኖ
ቹንም ፡ ባዶ ፡ ያደርጋሉ ፥ መስቴዎቹንም ፡ ይሰ
፲፫ ብራሉ ። የእስራኤልም ፡ ቤት ፡ ይታመንበት ፡

ከነበረው ፡ ከቤቴል ፡ እንዳፈረ ፥ እንዲሁ ፡
፲፬ ሞዓብ ፡ ከካሞሽ ፡ ያፍራል ። እናንተ ፡— እኛ ፡
ኃያላን ፡ በሰልፍም ፡ ጽኑዓን ፡ ነን ፡ እንዴት ፡
፲፭ ትላላችሁ ? ሞዓብ ፡ ፈርሶአል ፥ ከተሞቹም ፡
ጠፍተዋል ፥ የተመረጡትም ፡ ጕልማሶች ፡
ወደ ፡ መታረድ ፡ ወርደዋል ፥ ይላል ፡ ስሙ ፡
የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሆነ ፡ ንጉሥ ።
፲፮ የሞዓብ ፡ ጥፋት ፡ ሊመጣ ፡ ቀርቦአል ፡ መከራ
፲፯ ውም ፡ እጅግ ፡ ይፈጥናል ። በዙሪያው ፡ ያላ
ችሁ ፡ ሁሉ ፡ ስሙንም ፡ የምታውቁ ፡ ሁሉ ፡—
ብርቱው ፡ በትር ፥ የከበረው ፡ ሽመል ፥ እን
፲፰ ዴት ፡ ተሰበረ ! ብላችሁ ፡ አልቅሱለት ። በዲ
ቦን ፡ የምትኖሪ ፡ ሆይ ፥ ሞዓብን ፡ የሚያጠፋ ፡
ወጥቶብሻልና ፥ አምባሽንም ፡ሰብሮአልና ፡ ከከ
፲፱ ብርሽ ፡ ውረጂ ፡ በጥማትም ፡ ተቀመጪ ። በአ
ሮዔር ፡ የምትኖሪ ፡ ሆይ ፥ በመንገድ ፡ አጠገብ ፡
ቆመሽ ፡ ተመልከቺ ፤ የሸሸውንና ፡ ያመለጠች
፳ ውን ፡— ምን ፡ ሆኖአል ? ብለሽ ፡ ጠይቂ ። ሞዓ
ብም ፡ ፈርሶአልና ፡ አፈረ ፤ አልቅሱ ፡ ጩኹም ፤
ሞዓብ ፡ እንደ ፡ ተዘረፈ ፡ በአርኖን ፡ አጠገብ ፡
፳፩ አውሩ ። በሜዳ ፡ ላይ ፥ በሖሎን ፥ በያሳ ፥ በሜ
፳፪ ፍዓት ፡ ላይ ፥ በዲቦን ፥ በናባው ፥ በቤት ፡ ዲብ
፳፫ ላታይም ፡ ላይ ፥ በቂርያታይም ፥ በቤትጋሙል ፥
፳፬ በቤትምዖን ፡ ላይ ፥ በቂርዮት ፥ በባሶራ ፥ በሞ
ዓብም ፡ ምድር ፡ ከተሞች ፡ ሁሉ ፡ ቅርብና ፡
፳፭ ሩቅ ፡ በሆኑ ፡ ላይ ፡ ፍርድ ፡ መጥቶአል ። የሞ
ዓብ ፡ ቀንድ ፡ ተቈረጠ ፡ ክንዱም ፡ ተሰበረ ፥
ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
፳፮ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ኰርቶአልና ፡ አስከ
ሩት ፤ ሞዓብም ፡ በትፋቱ ፡ ላይ ፡ ይንከባለላል ፥
፳፯ ደግሞም ፡ መሳቂያ ፡ ይሆናል ። እስራኤል ፡
ለአንተ ፡ መሳቂያ ፡ አልሆነምን ? ወይስ ፡ በሌ
ቦች ፡ መካከል ፡ ተገኝቶአልን ? ስለ ፡ እርሱ ፡ በተ
፳፰ ናገርህ ፡ ጊዜ ፡ ራስህን ፡ ትነቀንቃለህ ። እናንተ ፡
በሞዓብ ፡ የምትኖሩ ፡ ሆይ ፥ ከተሞችን ፡ ትታ
ችሁ ፡ በዓለት ፡ ውስጥ ፡ ተቀመጡ ፥ በገደል ፡ አፉ
ፍም ፡ ቤትዋን ፡ እንደምትሠራ ፡ እንደ ፡ ርግብ ፡
፳፱ ሁኑ ። እጅግ ፡ እንደ ፡ ታበየ ፡ ስለ ፡ ሞዓብ ፡ ትዕ
ቢት ፡ ስለ ፡ ትምክህቱም ፡ ስለ ፡ ኵራቱም ፡ ስለ ፡
መኳደዱም ፡ ስለ ፡ ልቡም ፡ ትዕቢት ፡ ሰምተ
፴ ናል ። ቍጣው ፡ ምንም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አውቃ
ለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ፉከራው ፡ ምንም ፡
፴፩ አልሠራም ። ስለዚህ ፡ ለሞዓብ ፡ አለቅሳለሁ ፡
ለሞዓብም ፡ ሁሉ ፡ እጮኻለሁ ፤ ለቂርሔሬስ ፡
፴፪ ሰዎች ፡ አለቅሳለሁ ። አንቺ ፡ የሴባማ ፡ ወይን ፡
ሆይ ፥ ከኢያዜር ፡ ልቅሶ ፡ ይልቅ ፡ ለአንቺ ፡
አለቅሳለሁ ፤ ቅርንጫፎችሽ ፡ ባሕርን ፡ ተሻግረ
ዋል ፥ ወደ ፡ ኢያዜርም ፡ ባሕር ፡ ደርሰዋል ፤
አጥፊው ፡ በሰብልሽና ፡ በወይንሽ ፡ ላይ ፡ መጥ
፴፫ ቶአል ። ሐሤትና ፡ ደስታ ፡ ከፍሬያማው ፡ እር
ሻና ፡ ከሞዓብ ፡ ምድር ፡ ጠፍተዋል ፤ ጠጁን ፡
ከመጥመቂያው ፡ አጥፍቻለሁ ፤ ጠማቂውም ፡
በእልልታ ፡ አይጠምቅም ፥ እልልታቸውም ፡
፴፬ እልልታ ፡ አይሆንም ። ከሐሴቦን ፡ ጩኸት ፡
እስከ ፡ ኤልያሊና ፡ እስከ ፡ ያሀጽ ፡ ድረስ ፡ ድም
ፃቸውን ፡ ሰጥተዋል ፤ ከዞዓር ፡ እስከ ፡ ሖሮና
ይምና ፡ እስከ ፡ ዔግላት ፡ ሺሊሺያ ፡ ድረስ ፡ ይደ
ርሳል ፤ የኔምሬም ፡ ውኃ ፡ ደግሞ ፡ ይደርቃል ።
፴፭ በኮረብታው ፡ መስገጃ ፡ ላይ ፡ የሚሠዋውን ፡
ለአማልክቱም ፡ የሚያጥነውን ፡ ከሞዓብ ፡ አጠ
ፋለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
፴፮ ያተረፈው ፡ ትርፉ ፡ ጠፍቶበታልና ፤ ስለዚህ ፡
ልቤ ፡ ለሞዓብ ፡ እንደ ፡ እንቢልታ ፡ ይጮኻል ፥
ልቤም ፡ ለቂርሔሬስ ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ እንቢ
፴፯ ልታ ፡ ይጮኻል ። ራስ ፡ ሁሉ ፡ መላጣ ፡ ጢምም ፡
ሁሉ ፡ የተላጨ ፡ ነውና ፤ በእጅም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡
፴፰ ክትፋት ፡ በወገብም ፡ ላይ ፡ ማቅ ፡ አለና ። ሞዓ
ብን ፡ እንደማይወደድ ፡ ዕቃ ፡ ሰብሬአለሁና ፡
በሞዓብ ፡ ሰገነት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በአደባባዩም ፡ ላይ ፡
በሁሉም ፡ ቦታ ፡ ልቅሶ ፡ አለ ፥ ይላል ፡ እግዚአብ
፴፱ ሔር ። እንዴት ፡ ተገለበጠ ! በእፍረትም ፡ የተ
ነሣ ፡ ሞዓብ ፡ ጀርባውን ፡ እንዴት ፡ መለሰ ! ብላ
ችሁ ፡ አልቅሱ ። ሞዓብም ፡ በዙሪያው ፡ ላሉት ፡
ሁሉ ፡ መሳቂያና ፡ ድንጋጤ ፡ ይሆናል ።
፵ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— እነሆ ፥
እንደ ፡ ንስር ፡ ይበርራል ፡ ክንፉንም ፡ በሞዓብ ፡
፵፩ ላይ ፡ ይዘረጋል ። ከተሞቹ ፡ ተይዘዋል ፥ አም
ባዎቹም ፡ ተወስደዋል ፥ በዚያም ፡ ቀን ፡ የሞ
ዓብ ፡ ኃያላን ፡ ልብ ፡ ምጥ ፡ እንደ ፡ ያዛት ፡ ሴት ፡
፵፪ ልብ ፡ ይሆናል ። ሞዓብም ፡ በእግዚአብሔር ፡
ላይ ፡ ኰርቶአልና ፡ ሕዝብ ፡ ከመሆን ፡ ይጠፋል ።
፵፫ በሞዓብ ፡ የምትኖር ፡ ሆይ ፥ ፍርሃትና ፡ ጕድ
ጓድ ፡ ወጥመድም ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ አለ ፥ ይላል ፡
፵፬ እግዚአብሔር ። በሞዓብ ፡ ላይ ፡ የመጐብኘ
ትን ፡ ዓመት ፡ አመጣበታለሁና ፥ ይላል ፡ እግዚ
አብሔር ፤ በፍርሃት ፡ የሸሸ ፡ በጕድጓድ ፡ ውስጥ ፡
ይወድቃል ፥ ከጕድጓድም ፡ የወጣ ፡ በወጥመድ ፡
፵፭ ይያዛል ። የሸሹ ፡ ደክመው ፡ ከሐሴቦን ፡ ጥላ ፡
በታች ፡ ቆመዋል ፤ እሳት ፡ ከሐሴቦን ፡ ነበልባ
ልም ፡ ከሴዎን ፡ ወጥቶአል ፡ የሞዓብንም ፡ ማዕ
ዘን ፡ የሜትንም ፡ ልጆች ፡ አናት ፡ በልቶአል ።
፵፮ ሞዓብ ፡ ሆይ ፥ ወዮልህ ! የካሞሽ ፡ ወገን ፡ ጠፍ
ቶአል ፤ ወንዶች ፡ ልጆችህ ፡ ተማርከዋልና ፥
ሴቶች ፡ ልጆችህም ፡ ወደ ፡ ምርኮ ፡ ሄደዋልና ።
፵፯ ነገር ፡ ግን ፡ በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ የሞዓብን ፡
ምርኮ ፡ እመልሳለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
የሞዓብ ፡ ፍርድ ፡ እስከዚህ ፡ ድረስ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፱ ።

፩ ስለ ፡ አሞን ፡ ልጆች ፤ እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፡— ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የሉት
ምን ? ወይስ ፡ ወራሽ ፡ የለውምን ? ስለ ፡ ምን ፡
ሚልኮም ፡ ጋድን ፡ ወረሰ ? ሕዝቡስ ፡ በከተ
፪ ሞቹ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ተቀመጠ ? ስለዚህ ፥
እነሆ ፥ በአሞን ፡ ልጆች ፡ ከተማ ፡ በረባት ፡ ላይ ፡
የሰልፍ ፡ ውካታን ፡ የማሰማበት ፡ ዘመን ፡ ይመ
ጣል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ የፍርስራሽ ፡
ክምርም ፡ ትሆናለች ፥ ሴቶች ፡ ልጆችዋም ፡

በእሳት፡ይቃጠላሉ፥እስራኤልም፡የወረሱ
፫፤ ትን፡ይወርሳል፥ይላል፡እግዚአብሔር። ሐሴ
ቦን፡ሆይ፥ጋይ፡ፈርሳለችና፡አልቅሺላት፤
እናንተም፡የረባት፡ሴቶች፡ልጆች፡ሆይ፥
ሚልኮም፡ካህናቱና፡አለቆቹም፡በአንድነት፡
ይማረካሉና፡ጩኹ፥ማቅም፡ታጠቁ፥አል
ቅሱም፥በቅጥሮችም፡መካከል፡ተርዋርዋጡ።
፬፤ ማን፡ይመጣብኛል፡ብለሽ፡በመዝገብሽ፡የታ
መንሽ፡አንቺ፡ከዳተኛ፡ልጅ፡ሆይ፥በሸለቆ
ችሽ፥ውኃ፡በሚያረካቸው፡ሸለቆችሽ፥ስለ፡
፭፤ ምን፡ትመኪያለሽ? እነሆ፥በዙሪያሽ፡ካሉት፡
ሁሉ፡ዘንድ፡ፍርሃትን፡አመጣብሻለሁ፥ይላል፡
የሠራዊት፡ጌታ፡እግዚአብሔር፤እያንዳንዳ
ችሁም፡በፊታችሁ፡ወዳለው፡ስፍራ፡ትሰደ
ዳላችሁ፥የሚሸሹትንም፡የሚሰበስብ፡የለም።
፮፤ ነገር፡ግን፡ከዚያ፡በኋላ፡የአሞንን፡ልጆች፡
ምርኮ፡እመልሳለሁ፥ይላል፡እግዚአብሔር።
፯፤ ስለ፡ኤዶምያስ፤የሠራዊት፡ጌታ፡እግዚአ
ብሔር፡እንዲህ፡ይላል፦ በውኑ፡በቴማን፡
ጥበብ፡የለምን? ከብልሃተኞችስ፡ምክር፡ጠፍ
፰፤ ቶአልን? ጥበባቸውስ፡አልቆአልን? እናንተ፡
በድዳን፡የምትኖሩ፡ሆይ፥የዔሳውን፡ጥፋት፥
የምጐበኝበትን፡ጊዜ፥አመጣበታለሁና፡ሽሹ፥
ወደ፡ኋላ፡ተመለሱ፥በጥልቅም፡ውስጥ፡ተቀ
፱፤ መጡ። ወይን፡ለቃሚዎች፡ቢመጡብህ፥
ቃርሚያውን፡አይተዉልህምን? ሌቦችስ፡በሌ
ሊት፡ቢመጡ፥የሚያጠፉት፡እስኪበቃቸው፡
፲፤ ድረስ፡አይደለምን? እኔ፡ግን፡ዔሳውን፡ዐራ
ቍትሁት፥የተሸሸጉትንም፡ስፍራዎች፡ገለ
ጥሁ፥ይሸሸግም፡ዘንድ፡አይችልም፤ዘሩም፡
ወንድሞቹም፡ጎረቤቶቹም፡ጠፍተዋል፡እር
፲፩፤ ሱም፡የለም። ድሀ፡አደጎችህን፡ተው፥እኔም፡
በሕይወት፡አኖራቸዋለሁ፤መበለቶችህም፡
፲፪፤ በእኔ፡ይታመኑ። እግዚአብሔር፡እንዲህ፡
ይላልና፦ እነሆ፥ጽዋውን፡ያልተገባቸው፡
ሰዎች፡ጠጥተውታል፤አንተም፡ሳትቀጣ፡ትቀ
ራለህን? በእርግጥ፡ትጠጣለህ፡እንጂ፡ያለ፡
፲፫፤ ቅጣት፡አትቀርም። ባሶራ፡መደነቂያና፡መሰ
ደቢያ፡መረገሚያም፡እንድትሆን፡በራሴ፡
ምያለሁ፥ይላል፡እግዚአብሔር፤ከተሞች
ዋም፡ሁሉ፡ለዘላለም፡ባድማ፡ይሆናሉ።
፲፬፤ ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ወሬ፡ሰምቻለሁ፡
በአሕዛብም፡መካከል፦ ተሰብሰቡ፥በእርስ
ዋም፡ላይ፡ኑ፡ለሰልፍም፡ተነሡ፡የሚል፡
፲፭፤ መልእክተኛ፡ተልኮአል። እነሆ፥በአሕዛብ፡
ዘንድ፡የተጠቃህ፥በሰዎችም፡ዘንድ፡የተና
፲፮፤ ቀህ፡አድርጌሃለሁ። በዓለት፡ንቃቃት፡ውስጥ፡
የምትቀመጥ፥የተራራውን፡ከፍታ፡የምት
ይዝ፡ሆይ፥ድፍረትህና፡የልብህ፡ኵራት፡
አታልለውሃል። ቤትህን፡ምንም፡እንደ፡ንስር፡
ከፍ፡ብታደርግ፥ከዚያ፡አወርድሃለሁ፥ይላል፡
፲፯፤ እግዚአብሔር። ኤዶምያስም፡መደነቂያ፡ትሆ
ናለች፥የሚያልፍበትም፡ሁሉ፡ይደነቃል፥
ስለ፡መጣበትም፡መቅሠፍት፡ሁሉ፡ያፍዋጫ

፲፰፤ ባታል። ሰዶምና፡ገሞራ፡በእነርሱም፡አጠ
ገብ፡የነበሩት፡ከተሞች፡እንደ፡ተገለበጡ፥
ይላል፡እግዚአብሔር፥እንዲሁ፡በዚያ፡ሰው፡
አይቀመጥም፡የሰው፡ልጅም፡አይኖርበትም።
፲፱፤ እነሆ፥ከእርስዋ፡ዘንድ፡በቶሎ፡አባርራቸዋ
ለሁና፡በጠነከረው፡አምባ፡ላይ፡ከዮርዳኖስ፡
ትዕቢት፡ውስጥ፡እንደ፡አንበሳ፡ይወጣል፤የተ
መረጠውንም፡በእርስዋ፡ላይ፡እሾማለሁ፤
እንደ፡እኔ፡ያለ፡ማን፡ነው? ወይስ፡ለእኔ፡
ጊዜ፡የሚወስን፡ማን፡ነው? ወይስ፡ፊቴን፡
፳፤ የሚቃወም፡እረኛ፡ማን፡ነው? ስለዚህ፡እግ
ዚአብሔር፡በኤዶምያስ፡ላይ፡የመከረበትን፡
ምክር፥በቴማንም፡በሚኖሩ፡ሰዎች፡ላይ፡
ያሰበትን፡አሳብ፡ስሙ፤በእውነት፡የመንጋ፡
ትንንሾች፡ይጐተታሉ፤በእውነት፡ማደሪያቸ
፳፩፤ ውን፡ባድማ፡ያደርግባቸዋል። ከመውደቃ
ቸው፡ድምፅ፡የተነሣ፡ምድር፡ተናወጠች፥
የጩኸታቸውም፡ድምፅ፡በኤርትራ፡ባሕር፡
፳፪፤ ተሰማ። እነሆ፥እንደ፡ንስር፡ወጥቶ፡ይበር
ራል፡ክንፉንም፡በባሶራ፡ላይ፡ይዘረጋል፥በዚ
ያም፡ቀን፡የኤዶምያስ፡ኃያላን፡ልብ፡ምጥ፡
እንደ፡ያዛት፡ሴት፡ልብ፡ይሆናል።
፳፫፤ ስለ፡ደማስቆ፤ከፉ፡ወሬ፡ሰምተዋልና፡
ሐማትና፡አርፋድ፡አፈሩ፡ቀለጡም፤በባሕ
ርም፡ላይ፡ኀዘን፡አለ፥ታርፍም፡ዘንድ፡
፳፬፤ አትችልም። ደማስቆ፡ደከመች፡ትሸሽም፡
ዘንድ፡ዘወር፡አለች፡እንቅጥቅጥም፡ያዛት፥
እንደ፡ወላድም፡ሴት፡ጣርና፡ምጥ፡ያዛት።
፳፭፤ የተመሰገነችው፡ከተማ፥የደስታዬ፡ከተማ፥
፳፮፤ ሳትለቀቅ፡እንዴት፡ቀረች? ስለዚህ፡ጐበዛዝ
ትዋ፡በአደባባይዋ፡ላይ፡ይወድቃሉ፥በዚ
ያም፡ቀን፡ሰልፈኞች፡ሁሉ፡ይጠፋሉ፥
ይላል፡የሠራዊት፡ጌታ፡እግዚአብሔር።
፳፯፤ በደማስቆም፡ቅጥር፡ላይ፡እሳት፡አነድዳለሁ፡
የወልደ፡አዴርንም፡አዳራሾች፡ትበላለች።
፳፰፤ የባቢሎን፡ንጉሥ፡ናቡከደነፆር፡ስለ፡መታ፡
ስለ፡ቄዳርና፡ስለ፡አሶር፡መንግሥታት፤እግ
ዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፦ ተነሡ፡ወደ፡
ቄዳርም፡ውጡ፥የምሥራቅንም፡ልጆች፡
፳፱፤ አጥፉ። ድንኳናቸውንና፡መንጋቸውን፡ይወ
ስዳሉ፤መጋረጆቻቸውንና፡ዕቃቸውን፡ሁሉ፡
ግመሎቻቸውንም፡ለራሳቸው፡ይወስዳሉ፥
በዙሪያቸውም፡ሁሉ፡ጥፋትን፡ጥሩባቸው።
፴፤ እናንተ፡በአሶር፡የምትኖሩ፡ሆይ፥የባቢሎን፡
ንጉሥ፡ናቡከደነፆር፡ተማክሮባችኋልና፥አሳ
ብም፡አስቦባችኋልና፡ሽሹ፡ወደ፡ሩቅም፡
ሂዱ፡በጥልቅም፡ውስጥ፡ተቀመጡ፥ይላል፡
፴፩፤ እግዚአብሔር። ተነሡ፥ዕርፊት፡ወዳለበት፡
ተዘልሎም፡ወደ፡ተቀመጠው፥ደጅና፡መወ
ርወሪያ፡ወደሌለው፡ብቻውንም፡ወደ፡ተቀ
፴፪፤ መጠው፡ሕዝብ፡ውጡ። ግመሎቻቸው፡
ይበዘበዛሉ፡የእንስሶቻቸውም፡ብዛት፡ይማረ
ካል፤ጠጕራቸውንም፡በዙሪያ፡የሚላጩትን፡
ሰዎች፡ወደ፡ነፋሳት፡ሁሉ፡እበትናቸዋለሁ፤

ከዳርቻቸውም ፡ ሁሉ ፡ ጥፋት ፡ አመጣባቸዋ
፴፫፤ ለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። አሶርም ፡ የቀ
በሮ ፡ መኖሪያና ፡ የዘላለም ፡ ባድማ ፡ ትሆናለች ፤
በዚያም ፡ ሰው ፡ አይኖርም ÷ የሰው ፡ ልጅም ፡
አይቀመጥበትም ።

፴፬፤ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በሴዴቅያስ ፡ መንግሥት ፡
መጀመሪያ ፡ ስለ ፡ ኤላም ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡ ወደ ፡
ኤርምያስ ፡ የመጣው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡
፴፭፤ ይህ ፡ ነው ። የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ ዋና ፡ የኃይላቸው ፡
መሣሪያ ፡ የሆነውን ፡ የኤላምን ፡ ቀስት ፡ እሰብራ
፴፮፤ ለሁ ። ከአራቱም ፡ ከሰማይ ፡ ማዕዘናት ፡ አራ
ቱን ፡ ነፋሳት ፡ በኤላም ፡ ላይ ፡ አመጣለሁ ÷
ወደ ፡ እነዚያም ፡ ነፋሳት ፡ ሁሉ ፡ እበትናቸዋለሁ ፤
ከኤላም ፡ የተሰደዱ ፡ ሰዎች ፡ የማይደርሱበት ፡
፴፯፤ ሕዝብ ፡ አይገኝም ። በጠላቶቻቸውና ፡ ነፍሳ
ቸውን ፡ በሚሹአት ፡ ፊት ፡ ኤላምን ፡ አስደነግ
ጣለሁ ፤ ክፉ ፡ ነገርን ፡ እርሱም ፡ጽኑ ፡ ቍጣ
ዬን ፡ አመጣባቸዋለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤
እስካጠፋቸውም ፡ ድረስ ፡ በኋላቸው ፡ ሰይፍ ፡
፴፰፤ እሰድድባቸዋለሁ ፤ ዙፋኔንም ፡ በኤላም ፡ አኖ
ራለሁ ፡ ከዚያም ፡ ንጉሡንና ፡ አለቆቹን ፡ አጠ
፴፱፤ ፋለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ነገር ፡ ግን ፡
በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ የኤላምን ፡ ምርኮ ፡ እመል
ሳለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፶ ።

፩፤ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ከለዳውያን ፡ ምድር ፡
ስለ ፡ ባቢሎን ፡ በነቢዩ ፡ በኤርምያስ ፡ የተናገ
፪፤ ረው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ። በአሕዛብ ፡ መካከል ፡
ተናገሩ ፡ አውሩም ÷ ዓላማውንም ፡ አንሡ ፤
አውሩ ÷ አትደብቁ ፡— ባቢሎን ፡ ተወሰደች ÷
ቤል ፡ አፈረ ÷ ሜሮዳክ ፡ ደነገጠ ፤ ምስሎችዋ ፡
፫፤ አፈሩ ÷ ጣዖታትዋ ፡ ደነገጡ ፡ በሉ ። ሕዝብ ፡
ከሰሜን ፡ ወጥቶባታል ፡ ምድርዋንም ፡ ባድማ ፡
ያደርጋል ÷ የሚቀመጥባትም ፡ አይገኝም ፤
ከሰው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ እንስሳ ፡ ድረስ ፡ ሸሽ
፬፤ ተው ፡ ሄደዋል ። በዚያም ፡ ወራት ፡ በዚያም ፡
ጊዜ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ÷ የእስራኤል ፡
ልጆችና ፡ የይሁዳ ፡ ልጆች ፡ በአንድነት ፡ ሆነው ፡
ይመጣሉ ÷ እያለቀሱም ፡ መንገዳቸውን ፡ ይሄ
ዳሉ ÷ አምላካቸውንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይፈ
፭፤ ልጋሉ ። ፊታቸውንም ፡ ወደዚያ ፡ አቅንተው ፡—
ኑ ÷ ከቶ ፡ በማይረሳ ፡ በዘላለም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተጠጉ ፡ ብለው ፡ ስለ ፡
ጽዮን ፡ መንገድ ፡ ይጠይቃሉ ።

፮፤ ሕዝቤ ፡ የጠፉ ፡ በጎች ፡ ሆነዋል ፤ እረኞቻ
ቸው ፡ አሳቱአቸው ÷ በተራሮችም ፡ ላይ ፡ የተ
ቅበዘበዙ ፡ አደረጉአቸው ፤ ከተራራ ፡ ወደ ፡ ኮረ
፯፤ ብታ ፡ አለፉ ÷ በረታቸውንም ፡ ረሱ ። ያገኙአ
ቸው ፡ ሁሉ ፡ በሉአቸው ÷ ጠላቶቻቸውም ፡—
በጽድቅ ፡ ማደሪያ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ÷ በአ
ባቶቻቸው ፡ ተስፋ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡
ኃጢአት ፡ ስለ ፡ ሠሩ ፡ እኛ ፡ አልበደልንም ፡

፰፤ አሉ ። ከባቢሎን ፡ መካከል ፡ ሽሹ ÷ ከከለዳው
ያንም ፡ ምድር ፡ ውጡ ÷ በመንጎችም ፡ ፊት ፡
፱፤ እንደ ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፡ ሁኑ ። እነሆ ÷ ከሰ
ሜን ፡ ምድር ፡ የታላላቅ ፡ አሕዛብን ፡ ጉባኤ ፡
አስነሣለሁ ፡ በባቢሎንም ፡ ላይ ፡ አመጣቸዋ
ለሁ ፤ በእርስዋም ፡ ላይ ፡ ይሰለፋሉ ÷ ከዚያም ፡
ትወሰዳለች ፤ ፍላጾቻቸውም ፡ ባዶውን ፡ እንደማ
ይመለስ ፡ እንደ ፡ ብልህ ፡ ጀግና ፡ ፍላጻ ፡ ናቸው ።
፲፤ የከላውዴዎንም ፡ ምድር ፡ ትበዘበዛለች ÷ የሚ
በዘብዙአትም ፡ ሁሉ ፡ ይጠግባሉ ÷ ይላል ፡ እግ
ዚአብሔር ።

፲፩፤ ርስቴን ፡ የምትበዘብዙ ፡ እናንተ ፡ ሆይ ÷ ደስ ፡
ብሎአችኋልና ÷ ሐሤትንም ፡ አድርጋችኋልና ÷
በመስክ ፡ ላይም ፡ እንዳለች ፡ ጊደር ፡ ሆናችሁ ፡
ተቀናጥታችኋልና ÷ እንደ ፡ ብርቱዎችም ፡ ፈረ
፲፪፤ ሶች ፡ አሽካክታችኋልና ፡ እናታችሁ ፡ እጅግ ፡
ታፍራለች ÷ የወለደቻችሁም ፡ ትጐሰቍላለች ፤
እነሆ ÷ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ኋለኛይቱ ፡ ትሆ
ናለች ፤ ምድረ ፡ በዳና ፡ ደረቅ ፡ ምድር ፡ በረሀም ፡
፲፫፤ ትሆናለች ። ከእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ የተነሣ ፡
ባድማ ፡ ትሆናለች ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡ አይቀመጥበ
ትም ፤ በባቢሎንም ፡ በኩል ፡ የሚያልፍ ፡ ሁሉ ፡
ይደነቃል ፡ በመጣባትም ፡ መቅሠፍት ፡ ሁሉ ፡
፲፬፤ ያፍዋጫል ። እናንተ ፡ ቀስትን ፡ የምትገትሩ ፡
ሰዎች ፡ ሁሉ ÷ በባቢሎን ፡ ላይ ፡ በዙሪያዋ ፡ ተሰ
ለፉ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ኃጢአት ፡ ሠርታ
ለችና ፡ ወርውሩባት ፡ ፍላጾችንም ፡ አትንፈጉ ።
፲፭፤ የእግዚአብሔር ፡ በቀል ፡ ነውና ፡ በዙሪያዋ ፡
ጩኹባት ፤ እጅዋን ፡ ሰጠች ፤ ግንቦችዋ ፡ ወደቁ ፡
ቅጥሮችዋም ፡ ፈረሱ ፤ እርስዋን ፡ ተበቀሉ ፡
፲፮፤ እንደ ፡ ሠራችውም ፡ ሥሩባት ። ዘሪውንና ፡
በመከር ፡ ጊዜ ፡ ማጭድ ፡ የሚይዘውን ፡ ከባቢ
ሎን ፡ አጥፉ ፤ ከሚያስጨንቅ ፡ ሰይፍ ፡ ፊት ፡
እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ወገኑ ፡ ይመለሳል ፡ እያንዳ
ንዱም ፡ ወደ ፡ አገሩ ፡ ይሸሻል ።

፲፯፤ እስራኤል ፡ የባዘነ ፡ በግ ፡ ነው ፤ አንበሶች ፡ አሳ
ደዱት ፤ መጀመሪያ ፡ የአሦር ፡ ንጉሥ ፡ በላው ÷
በመጨረሻም ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደ
፲፰፤ ነፆር ፡ አጥንቱን ፡ ቈረጠመው ። ስለዚህ ፡
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የአሦርን ፡
ንጉሥ ፡ እንደ ፡ ቀጣሁ ፡ እንዲሁ ÷ እነሆ ÷ የባ
፲፱፤ ቢሎንን ፡ ንጉሥና ፡ ምድሩን ፡ እቀጣለሁ ። እስ
ራኤልንም ፡ ወደ ፡ ማሰማርያው ፡ እመልሳለሁ ÷
በቀርሜሎስና ፡ በባሳንም ፡ ላይ ፡ ይሰማራል ÷
ሰውነቱም ፡ በኤፍሬም ፡ ተራራና ፡ በገለዓድ ፡
፳፤ ላይ ፡ ትጠግባለች ። እነዚህን ፡ ያስቀረኋቸውን ፡
ይቅር ፡ እላቸዋለሁና ፡ በዚያን ፡ ወራት ፡ በዚ
ያም ፡ ዘመን ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ÷ የእስራ
ኤል ፡ በደል ፡ የይሁዳም ፡ ኃጢአት ፡ ይፈለጋል ፡
ምንም ፡ አይገኝም ።

፳፩፤ በምራታይም ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ በፋቁድም ፡ በሚ
ኖሩት ፡ ላይ ፡ ውጣ ፤ ግደላቸው ፡ ፈጽመህም ፡
አጥፋቸው ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ÷ እንዳዘዝ

፳፪ ሁህም ፡ ሁሉ ፡ አድርግ ። የሰልፍና ፡ የታላቅ ፡
፳፫ ጥፋት ፡ ውካታ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አለ ። የም
ድር ፡ ሁሉ ፡ መዶሻ ፡ እንዴት ፡ ደቀቀ ፡ እንዴትስ ፡
ተሰበረ ! ባቢሎንስ ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ እን
፳፬ ዴት ፡ በድማ ፡ ሆነች ! ባቢሎን ፡ ሆይ ÷ አጥ
ምጄብሻለሁ ፡ አንቺም ፡ ሳታውቂ ፡ ተይዘሻል ፤
ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ ስለ ፡ ተዋጋሽ ፡ ተገኝተ
፳፭ ሻል ፡ ተይዘሻማል ። የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ በከለዳውያን ፡ ምድር ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡
ሥራ ፡ አለውና ፡ እግዚአብሔር ፡ ዕቃ ፡ ቤቱን ፡
ከፍቶ ፡ የቍጣውን ፡ ዕቃ ፡ ጦር ፡ አውጥቶአል ።
፳፮ ከየበኩሉ ፡ በእርስዋ ፡ ላይ ፡ ውጡ ÷ ጎተራዎ
ችዋንም ፡ ክፈቱ ፤ እንደ ፡ ክምርም ፡ አድርጓት ፡
ፈጽማችሁም ፡ አጥፉአት ÷ አንዳችም ፡ አታስ
፳፯ ቀሩላት ። ወይፈኖችዋን ፡ ሁሉ ፡ እረዱ ÷ ወደ ፡
መታረድም ፡ ይውረዱ ፤ ቀናቸው ÷ የመጐብኘ
፳፰ ታቸው ፡ ጊዜ ÷ ደርሶአልና ፡ ወዮላቸው ! የአ
ምላካችንን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ በቀል ፡ የመ
ቅደሱንም ፡ በቀል ፡ በጽዮን ፡ ይነግሩ ፡ ዘንድ ፡
ሸሽተው ፡ ከባቢሎን ፡ አገር ፡ ያመለጡት ፡
ሰዎች ፡ ድምፅ ፡ ተሰምቶአል ።
፳፱ ቀስትን ፡ የሚገትሩትን ፡ ቀስተኞችን ፡ ሁሉ ፡
በባቢሎን ፡ ላይ ፡ ጥሩአቸው ፤ በዙሪያዋ ፡ ስፈ
ሩባት ፡ አንድም ፡ አያምልጥ ፤ በእስራኤል ፡
ቅዱስ ፡ ላይ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ኰርታለ
ችና ፡ እንደ ፡ ሥራዋ ፡ መጠን ፡ መልሱላት ÷
፴ እንዳደረገችም ፡ ሁሉ ፡ አድርጉባት ። ስለዚህ ፡
ጐበዛዝትዋ ፡ በአደባባይዋ ፡ ላይ ፡ ይወድቃሉ ÷
በዚያም ፡ ቀን ፡ ሰልፈኞችዋ ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋሉ ÷
፴፩ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ትዕቢተኛው ፡ ሆይ ÷
የመጐብኘትህ ፡ ጊዜ ÷ ቀንህ ፡ ደርሶአልና ፡
እነሆ ÷ በአንተ ፡ ላይ ፡ ነኝ ÷ ይላል ፡ የሠራዊት ፡
፴፪ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ትዕቢተኛው ፡ ተሰና
ክሎ ፡ ይወድቃል ፡ የሚያነሣውም ፡ የለም ፤ በከ
ተሞቹም ፡ ውስጥ ፡ እሳት ፡ አነድዳለሁ ÷ በዙሪ
ያውም ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ትበላለች ።
፴፫ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— የእስራኤል ፡ ልጆችና ፡ የይሁዳ ፡
ልጆች ፡ በአንድነት ፡ ተገፍተዋል ÷ የማረኳቸ
ውም ፡ ሁሉ ፡ በኃይል ፡ ይይዙአቸዋል ÷ ይለቅቁ
፴፬ አቸውም ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ ብለዋል ። ተቤዢአ
ቸው ፡ ብርቱ ፡ ነው ÷ ስሙም ፡ የሠራዊት ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ፤ ምድርንም ፡ ያሳርፍ ፡
ዘንድ ፡ በባቢሎንም ፡ የሚኖሩትን ፡ ያውክ ፡
ዘንድ ፡ ሙግታቸውን ፡ ፈጽሞ ፡ ይምዋገታል ።
፴፭ ሰይፍ ፡ በከለዳውያንና ፡ በባቢሎን ፡ በሚኖሩ ፡
ላይ ÷ በአለቆችዋና ፡ በጥበበኞችዋ ፡ ላይ ፡ አለ ÷
፴፮ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ሰይፍ ፡ በሚጓደዱት ፡
ላይ ፡ አለ ፡ ሰነፎችም ፡ ይሆናሉ ÷ ሰይፍም ፡
በኃያላኖችዋ ፡ ላይ ፡ አለ ፡ እነርሱም ፡ ይደነግ
፴፯ ጣሉ ። ሰይፍ ፡ በፈረሶቻቸውና ፡ በሰረገሎቻ
ቸው ፡ ላይ ፡ በመካከልዋም ፡ ባሉት ፡ ልዩ ፡
ልዩ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አለ ÷ እነርሱም ፡

ብዋ ፡ ላይ ፡ አለ ፡ ለብዝበዛም ፡ ይሆናል ።
፴፰ እርስዋ ፡ የተቀረጹ ፡ ምስሎች ፡ ምድር ፡ ናት ÷
እነርሱም ፡ በጣዖታት ፡ ይመካሉና ፡ ድርቅ ፡
በውኆችዋ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፡ እነርሱም ፡ ይደር
፴፱ ቃሉ ። ስለዚህ ፡ የምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊት ፡ ከተ
ኵላዎች ፡ ጋር ፡ ይቀመጡባታል ÷ ሰጐኖችም ፡
ይቀመጡባታል ፤ ሰውም ፡ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ለዘ
ላለም ፡ አይቀመጥባትም ÷ እስከ ፡ ልጅ ፡ ልጅም ፡
፵ ድረስ ፡ የሚኖርባት ፡ የለም ። ሰዶምንና ፡ ገሞ
ራን ፡ በአጠገባቸውም ፡ የነበሩትን ፡ ከተሞች ፡
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ገለበጣቸው ÷ ይላል ፡
እግዚአብሔር ÷ እንዲሁ ፡ ሰው ፡ በዚያ ፡ አይቀ
መጥም ፡ የሰውም ፡ ልጅ ፡ አይኖርባትም ።
፵፩ እነሆ ÷ ሕዝብ ፡ ከሰሜን ፡ ይመጣል ፡ ታላቅ
ሕዝብና ፡ ብዙ ፡ ነገሥታትም ፡ ከምድር ፡ ዳርቻ ፡
፵፪ ይነሣሉ ። ቀስትንና ፡ ጦርን ፡ ይይዛሉ ፤ ጨካ
ኞች ፡ ናቸው ፡ ምሕረትም ፡ አያደርጉም ፤ ድም
ፃቸው ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ ይተምማል ፡ በፈረሶ
ችም ፡ ላይ ፡ ይቀመጣሉ ፤ የባቢሎን ፡ ሴት ፡
ልጅ ፡ ሆይ ÷ ለሰልፍ ፡ እንደ ፡ ተዘጋጀ ፡ ሰው ፡
፵፫ እያንዳንዳቸው ፡ በአንቺ ፡ ላይ ፡ ተሰለፉ ። የባቢ
ሎን ፡ ንጉሥ ፡ ወሬአቸውን ፡ ሰምቶአል ÷
እጁም ፡ ደከማለች ÷ ጭንቀትም ፡ ይዞታል ÷
ምጥ ፡ ወላድ ፡ ሴትን ፡ እንደሚይዛት ፡ ጭንቀት ፡
፵፬ ይዞታል ። እነሆ ÷ ከእርስዋ ፡ ዘንድ ፡ በቶሎ ፡
አባርራቸዋለሁና ፡ በጠነከረው ፡ አምባ ፡ ላይ ፡
ከዮርዳኖስ ፡ ትዕቢት ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡
ይወጣል ፤ የተመረጠውንም ፡ በእርስዋ ፡ ላይ ፡
እሾመዋለሁ ፤ እንደ ፡ እኔ ፡ ያለ ፡ ማን ፡ ነው ?
ወይስ ፡ ለእኔ ፡ ጊዜ ፡ የሚወስን ፡ ማን ፡ ነው ? ወይስ ፡
፵፭ ፊቴን ፡ የሚቃወም ፡ እረኛ ፡ ማን ፡ ነው ? ስለ
ዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በባቢሎን ፡ ላይ ፡ የመከ
ረባትን ፡ ምክር ÷ በከለዳውያንም ፡ ምድር ፡
ላይ ፡ ያሰባትን ፡ አሳብ ፡ ስሙ ፤ በእውነት ፡ የመ
ንጋ ፡ ትንንሾች ፡ ይጐተታሉ ፤ በእውነት ፡ ማደ
፵፮ ሪያቸውን ፡ በድማ ፡ ያደርግባቸዋል ። ከባቢ
ሎን ፡ መያዝ ፡ ድምፅ ፡ የተነሣ ፡ ምድር ፡ ተናወ
ጠች ÷ ጩኸትም ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ዘንድ ፡
ተሰማ ።

ምዕራፍ ፡ ፶፩ ።

፩ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷
በባቢሎን ፡ ላይና ፡ በከለዳውያን ፡ ምድር ፡ በሚ
ኖሩት ፡ ላይ ፡ አጥፊውን ፡ ነፋስ ፡ አስነሣለሁ ።
፪ በባቢሎንም ፡ ላይ ፡ የሚያዘሩትን ፡ ሰዎች ፡ እሰድ
ዳለሁ ፡ እነርሱም ፡ ያዘሩአታል ÷ ምድርዋንም ፡
ባዶ ፡ ያደርጋሉ ፤ በመከራም ፡ ቀን ፡ በዙሪያዋ ፡
፫ ይከብቡአታል ። በወርዋሪው ፡ ላይ ፡ በጥሩርም ፡
በሚነሣው ፡ ላይ ፡ ቀስተኛው ፡ ቀስቱን ፡ ይገ
ትር ፤ ለጐበዛዝትዋ ፡ አትዘኑ ፡ ሠራዊትዋንም ፡
፬ ሁሉ ፡ አጥፉ ። በከለዳውያንም ፡ ምድር ፡ ተገ
ድለው ÷ በሚናዋም ፡ ላይ ፡ ተወግተው ፡ ይወ
ድቃሉ ።

ሠራው ፡ በደል ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ የተሞላች ፡
ብትሆን ÷ እስራኤልም ፡ ሆነ ፡ ይሁዳ ፡ በአም
ላኩ ፡ በሠራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
፮፤ አልተጣለም ። ከባቢሎን ፡ ውስጥ ፡ ሽሹ ÷ እያ
ንዳንዳችሁም ፡ ነፍሳችሁን ፡ አድኑ ፤ በበደልዋ ፡
አትጥፉ ÷ የእግዚአብሔር ፡ በቀል ፡ ጊዜ ፡
ነውና ÷ እርሱም ፡ ብድራትዋን ፡ ይከፍላታ
፯፤ ልና ። ባቢሎን ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ውስጥ ፡
ምድርን ፡ ሁሉ ፡ ያሰከረች ፡ የወርቅ ፡ ጽዋ ፡ ነበ
ረች ÷ አሕዛብም ፡ ከጠጅዋ ፡ ጠጥተዋል ፤ ስለ
፰፤ ዚህ ፡ አሕዛብ ፡ አብደዋል ። ባቢሎን ፡ በድን
ገት ፡ ወድቃ ፡ ጠፍታለች ፤ አልቅሱላት ÷ ትፈ
ወስም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለቍስልዋ ፡ መድኃኒት ፡
፱፤ ውሰዱላት ። ባቢሎንን ፡ ፈወስናት ÷ እርስዋ ፡
ግን ፡ አልተፈወሰችም ፤ ፍርድዋ ፡ እስከ ፡ሰማይ ፡
ደርሶአልና ÷ እስከ ፡ ደመናም ፡ ድረስ ፡ ከፍ ፡
ከፍ ፡ ብሎአልና ፡ ትታችኋት ፡ እያንዳንዳችን ፡
፲፤ ወደ ፡ አገራችን ፡ እንሂድ ። እግዚአብሔር ፡
ጽድቃችንን ፡ አውጥቶአል ፤ ኑ ÷ በጽዮን ፡ የአ
ምላካችንን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ እንናገር ።
፲፩፤ ፍላጻችን ፡ ሳሉ ፡ ጋሻዎችንም ፡ አዘጋጁ ፤ እግ
ዚአብሔር ፡ ያጠፋት ፡ ዘንድ ፡ አሳቡ ፡ በባቢ
ሎን ፡ ላይ ፡ ነውና ፡ የሜዶንን ፡ ነገሥታት ፡ መን
ፈስ ፡ አስነሥቶአል ፤ የእግዚአብሔር ፡ በቀል ፡
፲፪፤ የመቅደሱ ፡ በቀል ፡ ነውና ። በባቢሎን ፡ ቅጥር ፡
ዓላማውን ፡ አንሡበት ÷ ጥበቃን ፡ አጽኑ ÷ ተመ
ልካቾችን ፡ አቁሙ ÷ ድብቅ ፡ ጦር ፡ አዘጋጁ ።
እግዚአብሔር ፡ በባቢሎን ፡ በሚኖሩት ፡ ላይ ፡
የተናገረውን ፡ አስቦአልና ÷ አድርጎአልምና ።
፲፫፤ አንቺ ፡ በብዙ ፡ ውኃ ፡ አጠገብ ፡ የተቀመጥሽ ÷
በመዝገብም ፡ የበለጠግሽ ፡ ሆይ ÷ እንደ ፡ ስስ
፲፬፤ ትሽ ፡ መጠን ፡ ፍጻሜሽ ፡ ደርሶአል ። የሠራ
ዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡
በራሱ ፡ ምሎአል ፡— በእውነት ፡ ሰዎችን ፡ እንደ ፡
አንበጣ ፡ እሞላብሻለሁ ÷ እነርሱም ፡ ጩኸት ፡
ያነሡብሻል ።
፲፭፤ ምድርን ፡ በኃይሉ ፡ የፈጠረ ÷ ዓለሙን ፡ በጥ
በቡ ፡ የመሠረተ ÷ ሰማያትንም ፡ በማስተዋሉ ፡
፲፮፤ የዘረጋ ፡ እርሱ ፡ ነው ። ድምፁን ፡ ባሰማ ፡ ጊዜ ፡
ውኆች ፡ በሰማይ ፡ ይታወካሉ ÷ ከምድርም ፡
ዳር ፡ ደመናትን ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ፤ ለዝናብም ፡
መብረቅን ፡ ያደርጋል ÷ ነፋስንም ፡ ከቤተ ፡ መዛ
፲፯፤ ግብቱ ፡ ያወጣል ። ሰው ፡ ሁሉ ፡ እውቀት ፡
አጥቶ ፡ ሰንፎአል ÷ አንጥረኛም ፡ ሁሉ ፡ ከቀረ
ጸው ፡ ምስል ፡ የተነሣ ፡ አፍሮአል ፤ ቀልጦ ፡
የተሠራ ፡ ምስሉ ፡ ውሸት ፡ ነውና ÷ እስትንፋ
፲፰፤ ስም ፡ የላቸውምና ። እነርሱም ፡ ምናምንቴና ፡
የቀልድ ፡ ሥራ ፡ ናቸው ፤ በተጐበኙ ፡ ጊዜ ፡
፲፱፤ ይጠፋሉ ። የያዕቆብ ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ እንደ ፡
እነዚህ ፡ አይደለም ÷ እርሱ ፡ የሁሉ ፡ ፈጣሪ ፡
ነውና ፤ እስራኤልም ፡ የርስቱ ፡ ነገድ ፡ ነው ÷
ስሙም ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ።
፳፤ አንቺ ፡ መዶሻዬና ፡ የጦር ፡ መሣሪያዬ ፡ ነሽ ፤
በአንቺ ፡ አሕዛብን ፡ እሰባብራለሁ ፤ በአንቺም ፡
፳፩፤ መንግሥታትን ፡ አጠፋለሁ ፤ በአንቺ ፡ ፈረሱ
፳፪፤ ንና ፡ ፈረሰኛውን ፡ እሰባብራለሁ ፤ በአንቺም ፡
ሰረገላውንና ፡ በላዩ ፡ የሚቀመጠውን ፡ እሰባብ
ራለሁ ፤ በአንቺም ፡ ወንድንና ፡ ሴትን ፡ እሰባብ
ራለሁ ፤ በአንቺም ፡ ሽማግሌውንና ፡ ብላቴና
ውን ፡ እሰባብራለሁ ፤ በአንቺም ፡ ጕልማሳው
፳፫፤ ንና ፡ ቆንጆይቱን ፡ እሰባብራለሁ ፤ በአንቺም ፡
እረኛውንና ፡ መንጋውን ፡ እሰባብራለሁ ፤ በአን
ቺም ፡ አራሹንና ፡ ጥማጁን ፡ እሰባብራለሁ ፤
በአንቺም ፡ አለቆችንና ፡ ሹማምቶችን ፡ እሰባ
፳፬፤ ብራለሁ ። በጽዮን ፡ በዓይናችሁ ፡ ፊት ፡ ስለ ፡
ሠሩት ፡ ክፋታቸው ፡ ሁሉ ፡ በባቢሎንና ፡ በከ
ለዳውያን ፡ ምድር ፡ በሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ፍዳ
ቸውን ፡ እከፍላለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
፳፭፤ አንተ ፡ ምድርን ፡ ሁሉ ፡ የምታጠፋ ፡ አጥፊ ፡
ተራራ ፡ ሆይ ÷ እነሆ ÷ እኔ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ነኝ ÷
ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ እጄንም ፡ እዘረጋብሃ
ለሁ ÷ ከድንጋዮችም ፡ ላይ ፡ አንከባልልሃለሁ ÷
፳፮፤ የተቃጠለም ፡ ተራራ ፡ አደርግሃለሁ ። ከአን
ተም ፡ ለማዕዘንና ፡ ለመሠረት ፡ የሚሆን ፡ ድን
ጋይ ፡ አይወስዱም ÷ ለዘላለምም ፡ በድማ ፡ ትሆ
ናለህ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
፳፯፤ በምድር ፡ ላይ ፡ ዓላማን ፡ አንሡ ፡ በአሕዛብም ፡
መካከል ፡ መለከት ፡ ንፉ ÷ አሕዛብንም ፡ አዘጋ
ጁባት ፤ የአራራትንና ፡ የሚኒን ፡ የአስከናዝ
ንም ፡ መንግሥታት ፡ ሰብስቡባት ፡ አለቃንም ፡
በላይዋ ፡ አቁሙ ፤ እንደ ፡ ጠጕራም ፡ ኵብኵባ ፡
፳፰፤ ፈረሶችን ፡ በላይዋ ፡ አውጡ ። አሕዛብን ፡ የሜ
ዶንንም ፡ ነገሥታት ፡ አለቆችንም ፡ ሹማምቶ
ችንም ፡ ሁሉ ፡ የግዛታቸውንም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡
፳፱፤ አዘጋጁባት ። ማንም ፡ እንዳይቀመጥባት ፡ የባ
ቢሎንን ፡ ምድር ፡ በድማ ፡ ያደርጋት ፡ ዘንድ ፡
የእግዚአብሔር ፡ አሳብ ፡ በባቢሎን ፡ ላይ ፡ ጸን
ቶአልና ፡ ምድር ፡ ተናውጣለች ፡ ታመመችም ።
፴፤ የባቢሎን ፡ ኃያላን ፡ መዋጋትን ፡ ትተዋል ፡ በአ
ምባዎቻቸውም ፡ ውስጥ ፡ ተቀምጠዋል ፤ ኃይ
ላቸውም ፡ ጠፍቶአል ፡ እንደ ፡ ሴቶችም ፡ ሆነ
ዋል ፤ ማደሪያዎችዋም ፡ ነድደዋል ፡ መወርወ
፴፩፤ ፴፪፤ ሪያዎችዋም ፡ ተሰብረዋል ። ከዳር ፡ እስከ ፡
ዳር ፡ ድረስ ፡ ከተማው ፡ እንደ ፡ ተያዘች ÷ መል
ካዎችዋም ፡ እንደ ፡ ተያዙ ÷ ቅጥርዋም ፡ በእ
ሳት ፡ እንደ ፡ ተቃጠለ ÷ ሰልፈኞችም ፡ እንደ ፡
ደነገጡ ፡ ለባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ይነግር ፡ ዘንድ ፡
ወሬኛው ፡ ወሬኛውን ፡ መልእክተኛውም ፡ መል
እክተኛውን ፡ ሊገናኝ ፡ ይሮጣል ።
፴፫፤ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— አውድማ ፡ እንደ ፡
ተረገጠ ፡ ጊዜ ÷ እንዲሁ ፡ የባቢሎን ፡ ልጅ ፡
ናት ፤ ጥቂት ፡ ቈይታ ፡ የመከር ፡ ጊዜ ፡ ይደርስ
፴፬፤ በታል ። የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡
በላኝ ÷ ከፋፈለኝም ÷ እንደ ፡ ባዶ ፡ ዕቃም ፡
አደረገኝ ÷ እንደ ፡ ዘንዶም ፡ ዋጠኝ ÷ ከሚጣፍ
ጠውም ፡ ምግቤ ፡ ሆዱን ፡ ሞላ ÷ እኔንም ፡
፴፭፤ ጣለኝ ። በጽዮን ፡ የምትቀመጥ ፡— በእኔና ፡

በሥጋዬ ፡ የተደረገ ፡ ግፍ ፡ በባቢሎን ፡ ላይ ፡
ይሁን ፡ ትላለች ፤ ኢየሩሳሌምም ፡— ደሜ ፡ በከ
ለዳውያን ፡ ምድር ፡ በሚኖሩት ፡ ላይ ፡ ይሁን ፡
፴፮፤ ትላለች ። ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እነሆ ፡ እምዋገትልሻለሁ ፡ በቀልሽ
ንም ፡ እበቀልልሻለሁ ፤ ባሕርዋንም ፡ ድርቅ ፡
አደርገዋለሁ ፡ ምንጭዋንም ፡ አደርቃለሁ ።
፴፯፤ ባቢሎንም ፡ የድንጋይ ፡ ቍልልና ፡ የቀበሮ ፡
ማደሪያ ፡ መደነቂያም ፡ ማፍዋጫም ፡ ትሆናለች ÷
፴፰፤ የሚቀመጥባትም ፡ ሰው ፡ አይገኝም ። በአን
ድነትም ፡ እንደ ፡ አንበሶች ፡ ያገሣሉ ÷ እንደ ፡
፴፱፤ አንበሳም ፡ ደቦሎች ፡ ያጕረመርማሉ ። በሞቃ
ቸው ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ እንዲላቸው ፡ ለዘላለምም ፡
እንቀላፍተው ፡ እንዳይነቁ ፡ የመጠጥ ፡ ግብዣ ፡
አደርግላቸዋለሁ ፡ አሰክራቸውማለሁ ÷ ይላል ፡
፵፤ እግዚአብሔር ። እንደ ፡ ጠቦቶችና ፡ እንደ ፡
አውራ ፡ በጎች ፡ እንደ ፡ አውራ ፡ ፍየሎችም ፡
ወደ ፡ መታረድ ፡ አወርዳቸዋለሁ ።
፵፩፤ ሼሻክ ፡ እንዴት ፡ ተያዘች ! የምድርም ፡
ሁሉ ፡ ምስጋና ፡ እንዴት ፡ ተወሰደች ! ባቢሎ
ንም ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ መደነቂያ ፡ እንዴት ፡
፵፪፤ ሆነች ! ባሕር ፡ በባቢሎን ፡ ላይ ፡ ወጣ ፡ በሞገ
፵፫፤ ዱም ፡ ብዛት ፡ ተከደነች ። ከተሞችዋ ፡ ባድማና ፡
ደረቅ ፡ ምድር ፡ ምድረ ፡ በዳም ÷ ሰውም ፡ የማ
ይቀመጥበት ፡ የሰውም ፡ ልጅ ፡ የማያልፍበት ፡
፵፬፤ ምድር ፡ ሆኑ ። በባቢሎንም ፡ ውስጥ ፡ ቤልን ፡
እቀጣለሁ ፡ የዋጠውንም ፡ ከአፉ ፡ አስተፋዋለሁ ፤
አሕዛብም ፡ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አይሰ
በሰቡም ÷ የባቢሎንም ፡ ቅጥር ፡ ይወድቃል ።
፵፭፤ ሕዝቤ ፡ ሆይ ÷ ከመካከልዋ ፡ ውጡ ፡ እያንዳ
ንዳችሁም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጽኑ ፡ ቍጣ ፡
፵፮፤ ራሳችሁን ፡ አድኑ ። በምድርም ፡ ከሚሰማ ፡
ወሬ ፡ የተነሣ ፡ አትፍሩ ፡ ልባችሁም ፡ የዛለ ፡
አይሁን ፤ በአንድ ፡ ዓመት ፡ ወሬ ፡ ይመጣል ÷
ከዚያም ፡ በኋላ ፡ በሌላው ፡ ዓመት ፡ ወሬ ÷ በም
ድርም ፡ ላይ ፡ ግፍ ፡ ይመጣል ÷ አለቃም ፡ በአ
፵፯፤ ለቃ ፡ ላይ ፡ ይነሣል ። ስለዚህ ÷ እነሆ ÷ የተቀ
ረጹትን ፡ የባቢሎን ፡ ምስሎች ፡ የምቀጣበት ፡
ዘመን ፡ ይመጣል ÷ ምድርዋም ፡ ሁሉ ፡ ታፍራ
ለች ፤ ተወግተውም ፡ የሞቱት ፡ ሁሉ ፡ በመካከ
፵፰፤ ልዋ ፡ ይወድቃሉ ። አጥፊዎች ፡ ከሰሜን ፡ ይመ
ጡባታልና ፡ ሰማይና ፡ ምድር ፡ በእነርሱም ፡
ያለው ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ባቢሎን ፡ እልል ፡ ይላሉ ÷
፵፱፤ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ባቢሎንም ፡ ከእስራ
ኤል ፡ ተወግተው ፡ የሞቱት ፡ እንዲወድቁ ፡
እንዳደረገች ÷ እንዲሁ ፡ በባቢሎን ፡ ከምድሩ ፡
ሁሉ ፡ ተወግተው ፡ የሞቱት ፡ ይወድቃሉ ።
፶፤ ከሰይፍ ፡ ያመለጣችሁ ፡ ሆይ ÷ ሂዱ ÷ አት
ቁሙ ፤ እግዚአብሔርን ፡ ከሩቅ ፡ አስቡ ÷ ኢየ
፶፩፤ ሩሳሌምንም ፡ በልባችሁ ፡ አስቡ ። ስድብን ፡
ስለ ፡ ሰማን ፡ አፍረናል ፤ ባዕዳን ፡ ሰዎችም ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ገብተዋ
ልና ፡ ነውር ፡ ፊታችንን ፡ ከድኖታል ። ስለዚህ ÷ ፶፪፤
እነሆ ÷ የተቀረጹትን ፡ ምስሎችዋ ፡ የምቀጣ
በት ፡ ዘመን ፡ ይመጣል ÷ ይላል ፡ እግዚአብ
ሔር ፤ በምድርዋም ፡ ሁሉ ፡ የተወጉት ፡ ያንቋ
ርራሉ ። ባቢሎን ፡ ምንም ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ብት ፶፫፤
ወጣ ÷ የኀይልዋንም ፡ ከፍታ ፡ ብታጸና ÷ ከእኔ ፡
ዘንድ ፡ አጥፊዎች ፡ ይመጡባታል ÷ ይላል ፡ እግ
ዚአብሔር ።
ከባቢሎን ፡ ጩኸት ÷ ከከለዳውያንም ፡ ፶፬፤
ምድር ፡ የታላቅ ፡ ጥፋት ፡ ድምፅ ፡ ተሰምቶ
አል ። እግዚአብሔር ፡ ባቢሎንን ፡ አጥፍቶአታ ፶፭፤
ልና ÷ ከእርስዋም ፡ ታላቁን ፡ ድምፅ ፡ ዝም ፡ አሰኝ
ቶአልና ፤ ሞገዳቸውም ፡ እንደ ፡ ብዙ ፡ ውኆች ፡
ይተምማል ÷ የድምፃቸውም ፡ ጩኸት ፡ ተሰ
ምቶአል ። አጥፊው ፡ በባቢሎን ፡ ላይ ፡ መጥ ፶፮፤
ቶባታልና ÷ ኃያላኖችዋ ፡ ተያዙ ÷ ቀስታቸ
ውም ፡ ተሰባበረ ፤ እግዚአብሔር ፡ ፍዳን ፡ የሚ
ከፍል ፡ አምላክ ፡ ነውና ÷ ፍዳንም ፡ በእርግጥ ፡
ይከፍላል ። መሳፍንቶችዋንና ፡ ጥበበኞችዋ ፶፯፤
ንም ÷ አለቆችዋንና ፡ ሹማምቶችዋን ፡ ኃያ
ላኖችዋንም ፡ አሰክራለሁ ÷ ለዘላለምም ፡ አን
ቀላፍተው ፡ አይነቁም ÷ ይላል ፡ ስሙ ፡ የሠራ
ዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ የተባለው ፡ ንጉሥ ።
የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ፶፰፤
ይላል ፡— ሰፊው ፡ የባቢሎን ፡ ቅጥር ፡ ፈጽሞ ፡
ይፈርሳል ፡ ረጃጅሞችም ፡ በሮችዋ ፡ በእሳት ፡
ይቃጠላሉ ፤ የወገኖችም ፡ ድካም ፡ ከንቱ ፡ ትሆ
ናለች ÷ የአሕዛብም ፡ ሥራ ፡ ለእሳት ፡ ትሆና
ለች ፤ እነርሱም ፡ ይደክማሉ ።
የመሕሤያ ፡ ልጅ ፡ የኔርያ ፡ ልጅ ፡ ሠራያ ፡ ፶፱፤
የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ሴዴቅያስ ፡ በነገሠ ፡ በአራተ
ኛው ፡ ዓመት ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡
በሄደ ፡ ጊዜ ፡ ነቢዩ ፡ ኤርምያስ ፡ ያዘዘው ፡ ቃል ፡
ይህ ፡ ነው ። ሠራያም ፡ የቤት ፡ አዛዥ ፡ ነበረ ።
በባቢሎንም ፡ ላይ ፡ የሚመጣውን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ፷፤
ሁሉ ÷ ስለ ፡ ባቢሎን ፡ የተጻፈውን ፡ ይህን ፡
ቃል ፡ ሁሉ ÷ ኤርምያስ ፡ በመጽሐፍ ፡ ላይ ፡
ጻፈው ። ኤርምያስም ፡ ሠራያን ፡ እንዲህ ፡ ፷፩፤
አለው ፡— ወደ ፡ ባቢሎን ፡ በገባህ ፡ ጊዜ ፡ እይ ÷
ይህንም ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ አንብብና ፡— አቤቱ ÷ ፷፪፤
ከሰው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ እንስሳ ፡ ድረስ ፡ ማንም ፡
እንዳይቀመጥባት ÷ ለዘላለምም ፡ ባድማ ፡ እን
ድትሆን ፡ ታጠፋት ፡ ዘንድ ፡ በዚህች ፡ ስፍራ ፡
ላይ ፡ ተናግረሃል ፡ በል ። ይህንም ፡ መጽሐፍ ፡ ፷፫፤
ማንበብ ፡ ከፈጸምህ ፡ በኋላ ÷ ድንጋይን ፡ እሰ
ርበት ፡ በኤፍራጥስም ፡ ውስጥ ፡ ጣለው ፤ አን ፷፬፤
ተም ፡— እኔ ፡ ከማመጣባት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ የተ
ነሣ ፡ እንዲሁ ፡ ባቢሎን ፡ ትሰጥማለች ፡ አትነሣ
ምም ፡ በል ።
የኤርምያስ ፡ ቃል ፡ እስከዚህ ፡ ድረስ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፶፪ ።

፩ ሴዴቅያስ ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የሀያ ፡
አንድ ፡ ዓመት ፡ ጐልማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌ
ምም ፡ አሥራ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ እና
ቱም ፡ አሚጣል ፡ የተባለች ፡ የሊብና ፡ ሰው ፡ የኤር
፪ ምያስ ፡ ልጅ ፡ ነበረች ። ኢዮአቄምም ፡ እንዳደረገ ፡
ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ።
፫ ከፊቱም ፡ አውጥቶ ፡ እስኪጥላቸው ፡ ድረስ ፡
ይህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በኢየሩሳሌምና ፡
በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ሆኖአልና ፤ ሴዴቅያስም ፡ በባቢ
ሎን ፡ ንጉሥ ፡ ላይ ፡ ዐመፀ ።
፬ ሴዴቅያስም ፡ በነገሠ ፡ በዘጠነኛው ፡ ዓመት ፡
በአሥረኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአሥረኛው ፡
ቀን ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆርና ፡ ሠራ
ዊቱ ፡ ሁሉ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ መጥተው ፡
ከበቡአት ፡ በዙሪያዋም ፡ ዕርድ ፡ አደረገ ።
፭ ከተማይቱም ፡ እስከ ፡ ንጉሡ ፡ እስከ ፡ ሴዴቅያስ ፡
እስከ ፡ አሥራ ፡ አንደኛው ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ተከ
፮ ብባ ፡ ነበር ። በአራተኛውም ፡ ወር ፡ በዘጠነ
ኛው ፡ ቀን ፡ በከተማይቱ ፡ ራብ ፡ ጸንቶ ፡ ነበር ፥
፯ ለአገሩም ፡ ሰዎች ፡ እንጀራ ፡ ታጣ ። ከተማይ
ቱም ፡ ተሰበረች ፥ ሰልፈኞችም ፡ ሁሉ ፡ ሸሹ ፥
በሁለቱም ፡ ቅጥር ፡ መካከል ፡ ባለው ፡ በር ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ አትክልት ፡ በሚወስደው ፡ መንገድ ፡
በሌሊት ፡ ከከተማይቱ ፡ ወጡ ። ከለዳውያንም ፡
በከተማይቱ ፡ ዙሪያ ፡ ነበሩ ፤ በዓረባም ፡ መን
፰ ገድ ፡ ሄዱ ። የከለዳውያንም ፡ ሠራዊት ፡ ንጉ
ሡን ፡ ተከታተሉት ፥ በኢያሪኮም ፡ ሜዳ ፡ ሴዴ
ቅያስን ፡ ያዙ ፤ ሠራዊቱም ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡
፱ ዘንድ ፡ ተበትነው ፡ ነበር ። ንጉሡንም ፡ ይዘው ፡
የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ወዳለበት ፡ በሐማት ፡
ምድር ፡ ወዳለችው ፡ ወደ ፡ ሪብላ ፡ አመጡት ፤
እርሱም ፡ ፍርድን ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ተናገረ ።
፲ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ የሴዴቅያስን ፡ ልጆች ፡
በፊቱ ፡ ገደላቸው ፥ የይሁዳንም ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡
፲፩ ደግሞ ፡ በሪብላ ፡ ገደላቸው ። የሴዴቅያስንም ፡
ዓይኖች ፡ አወጣ ፤ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ በሰን
ሰለት ፡ አሰረው ፡ ወደ ፡ ባቢሎንም ፡ ወሰደው ፥
እስኪሞትም ፡ ድረስ ፡ በግዞት ፡ ቤት ፡ አኖረው ።
፲፪ በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ በናቡከደነፆር ፡ በአሥራ ፡
ዘጠነኛው ፡ ዓመት ፡ በአምስተኛው ፡ ወር ፡ ከወ
ሩም ፡ በአሥረኛው ፡ ቀን ፡ በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡
ፊት ፡ የቆመው ፡ የዘበኞቹ ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡
፲፫ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጣ ። የእግዚአብሔርን ፡
ቤትና ፡ የንጉሡን ፡ ቤት ፡ አቃጠለ ፤ የኢየሩሳሌ
ምንም ፡ ቤቶች ፡ ሁሉ ፥ ታላላቆችን ፡ ቤቶች ፡
፲፬ ሁሉ ፥ በእሳት ፡ አቃጠለ ። ከዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡
ጋር ፡ የነበረው ፡ የከለዳውያን ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡
የኢየሩሳሌምን ፡ ቅጥር ፡ ሁሉ ፡ ዙሪያዋን ፡ አፈ
፲፭ ረሱ ። የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡ የሕዝ
ቡን ፡ ድኆች ፥ በከተማም ፡ ውስጥ ፡ የቀረውን ፡
ሕዝብ ፥ ሸሽተውም ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡
የተጠጉትን ፥ የሕዝቡንም ፡ ቅሬታ ፡ አፈለሰ ።

፲፮ የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡ ከአገሩ ፡
ድኆች ፡ ወይን ፡ ተካዮችና ፡ አራሾች ፡ እንዲ
ሆኑ ፡ አስቀረ ።
፲፯ ከለዳውያንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የነ
በሩትን ፡ የናስ ፡ ዓምዶች ፡ በእግዚአብሔርም ፡
ቤት ፡ የነበሩትን ፡ መቀመጫዎችና ፡ የናሱን ፡
ኵሬ ፡ ሰባበሩ ፥ ናሱንም ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡
፲፰ ወሰዱ ። ምንቸቶቹንና ፡ መጫሪያዎችንም ፡ መኰ
ስተሪያዎችንና ፡ ድስቶችን ፡ ጭልፋዎችንም ፡
የሚያገለግሉበትንም ፡ የናስ ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ወሰዱ ።
፲፱ የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ ጽዋዎቹንና ፡ ማንደጃዎቹን ፡
ድስቶቹንና ፡ ምንቸቶችን ፡ መቅረዞችንና ፡ ጭል
ፋዎቹን ፡ መንቀሎችንም ፥ የወርቁን ፡ ዕቃ ፡ በወ
ርቅ ፥ የብሩንም ፡ ዕቃ ፡ በብር ፡ አድርጎ ፥ ወሰደ ።
፳ ንጉሡ ፡ ሰሎሞንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
ያሠራቸውን ፡ ሁለቱን ፡ ዓምዶች ፥ አንዱንም ፡
ኵሬ ፥ ከመቀመጫዎቹም ፡ በታች ፡ የነበሩትን ፡
አሥራ ፡ ሁለቱን ፡ የናስ ፡ በሬዎች ፡ ወሰደ ፤ ለእ
ነዚህ ፡ ዕቃዎች ፡ ሁሉ ፡ ናስ ፡ ሚዛን ፡ አልነበ
፳፩ ረም ። ዓምዶቹም ፥ የአንዱ ፡ ዓምድ ፡ ቁመት ፡
አሥራ ፡ ስምንት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ የዙሪያውም ፡
መጠን ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፤ ውፍ
ረቱም ፡ አራት ፡ ጣት ፡ ያህል ፡ ነበረ ፥ ባዶም ፡
፳፪ ነበረ ። የናሱም ፡ ጕልላት ፡ በላዩ ፡ ነበረ ፤ የአ
ንዱም ፡ ጕልላት ፡ ቁመት ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡
ነበረ ፥ በጕልላቱም ፡ ላይ ፡ በዙሪያው ፡ ሁሉ ፡
ከናስ ፡ የተሠሩ ፡ መረበብና ፡ ሮማኖች ፡ ነበሩ
በት ፤ በሁለተኛውም ፡ ዓምድ ፡ ደግሞ ፡ እንደ
ዚህ ፡ ያለ ፡ ነገርና ፡ ሮማኖች ፡ ነበሩበት ።
፳፫ በስተ ፡ ውጭም ፡ ዘጠና ፡ ስድስት ፡ ሮማኖች ፡
ነበሩ ። በመረበቡም ፡ ዙሪያ ፡ የነበሩ ፡ ሮማኖች ፡
ሁሉ ፡ አንድ ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።
፳፬ የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ ታላቁን ፡ ካህን ፡ ሠራ
ያን ፡ ሁለተኛውንም ፡ ካህን ፡ ሶፎንያስን ፡ ሦስ
፳፭ ቱንም ፡ በረኞች ፡ ወሰደ ፤ ከከተማይቱም ፡
በሰልፈኞች ፡ ላይ ፡ ተሾመው ፡ ከነበሩት ፡ አን
ዱን ፡ ጃንደረባ ፥ በከተማይቱም ፡ ከሚገኙት ፡
በንጉሡ ፡ ፊት ፡ ከሚቆሙት ፡ ሰባቱን ፡ ሰዎች ፥
የአገሩንም ፡ ሕዝብ ፡ የሚያሰልፈውን ፡ የሠራ
ዊቱን ፡ አለቃ ፡ ጸሐፊ ፥ በከተማይቱም ፡ ከተ
ገኙት ፡ ከአገሩ ፡ ሕዝብ ፡ ስድሳ ፡ ሰዎች ፡ ወሰደ ።
፳፮ የዘበኞቹም ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡ ወስዶ ፡ የባ
ቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ወዳለበት ፡ ወደ ፡ ሪብላ ፡ አመ
፳፯ ጣቸው ። የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ መታቸው ፥
በሐማትም ፡ ምድር ፡ ባለችው ፡ በሪብላ ፡ ገደ
ላቸው ። እንዲሁ ፡ ይሁዳ ፡ ከአገሩ ፡ ተማረከ ።
፳፰ ናቡከደነፆር ፡ የማረከው ፡ ሕዝብ ፡ ይህ ፡
ነው ፤ በሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ ሀያ ፡
፳፱ ሦስት ፡ አይሁድ ፤ ናቡከደነፆርም ፡ በአሥራ ፡
ስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ ስምንት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡
ሁለት ፡ ነፍስ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ማርከአል ፤
፴ በናቡከደነፆር ፡ በሀያ ፡ ሦስተኛው ፡ ዓመት ፡
የዘበኞቹ ፡ አለቃ ፡ ናቡዘረዳን ፡ ከአይሁድ ፡
ሰባት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ አምስት ፡ ነፍስ ፡ ማርከ

አል ፤ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ።

፴፩ ፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ዮአኪን ፡ በተማረከ ፡ በሠላሳ ፡ ሰባተኛው ፡ ዓመት ÷ በአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በሀያ ፡ አምስተኛው ፡ ቀን ÷ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ዮርማሮዴክ ፡ በነገሠ ፡ በአንደኛው ፡ ዓመት ፡ የይሁዳን ፡ ንጉሥ ፡ የዮአኪንን ፡ ራስ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገ ፡ ከወህኒም ፡ አወጣው ፤ ፴፪ ፤ በመልካምም ፡ ተናገረው ÷ ዙፋኑንም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በባቢሎን ፡ ከነበሩት ፡ ነገሥታት ፡ ዙፋን ፡ በላይ ፡ አደረገለት ። ፴፫ ፤ በወህኒም ፡ ውስጥ ፡ ለብሶት ፡ የነበረውን ፡ ልብስ ፡ ለወጠለት ÷ ዮአኪንም ፡ በሕይወቱ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ሁልጊዜ ፡ እንጀራ ፡ ይበላ ፡ ነበር ። ፴፬ ፤ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ በሕይወቱ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ የዘወትር ፡ ቀለብ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ይሰጠው ፡ ነበር ።

# ሰቆቃወ ፡ ኤርምያስ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ ፤ አሌፍ ። ሕዝብ ፡ ሞልቶባት ፡ የነበረች ፡ ከተማ ፡ ብቻዋን ፡ እንዴት ፡ ተቀመጠች !
በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ታላቅ ፡ የነበረች ፡ እንደ ፡ መበለት ፡ ሆናለች ፤
በአውራጆች ፡ መካከል ፡ ልዕልት ፡ የነበረች ፡ ተገዢ ፡ ሆናለች ።

፪ ፤ ቤት ። በሌሊት ፡ እጅግ ፡ ታለቅሳለች ÷ እንባዋም ፡ በጕንጭዋ ፡ ላይ ፡ አለ ፤
ከውሽሞችዋ ፡ ሁሉ ፡ የሚያጽናናት ፡ የለም ፤
ወዳጆችዋ ፡ ሁሉ ፡ ወነጀሉአት ፡ ጠላቶችም ፡ ሆኑአት ።

፫ ፤ ጋሜል ። ይሁዳ ፡ ስለ ፡ መጨነቅና ፡ ስለ ፡ ባርነት ፡ ብዛት ፡ ተማረከች ፤
በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ተቀመጠች ፡ ዕረፍትም ፡ አላገኘችም ፤
የሚያስጨንቁአት ፡ ሁሉ ፡ ተጨንቃ ፡ አገኙአት ።

**፬፤** ዳሌጥ ። ወደ ፡ ዓመት ፡ በዓልም ፡ የሚመጣ ፡ የለ ምና ፡ የጽዮን ፡ መንገዶች ፡ አለቀሱ ፤
በሮችዋ ፡ ሁሉ ፡ ፈርሰዋል ፡ ካህናቶችዋም ፡ እየጮኹ ፡ ያለቅሳሉ ፤
ደናግሎችዋም ፡ ተጨነቁ ፡ እርስዋም ፡ በምሬት ፡ አለች ።

**፭፤** ሄ ። ስለ ፡ ኃጢአትዋ ፡ ብዛት ፡ እግዚአብሔር ፡ አስጨንቆአታልና ፡
አስጨናቂዎችዋ ፡ ራስ ፡ ሆኑ ፡ ጠላቶችዋም ፡ ተከናወነላቸው ፤
ሕፃናቶችዋ ፡ በአስጨናቂዎች ፡ ፊት ፡ ተማርከ ዋል ።

**፮፤** ዋው ። ከጽዮን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ውበትዋ ፡ ሁሉ ፡ ወጥቶአል ፤
አለቆችዋ ፡ ማሰማርያ ፡ እንደማያገኙ ፡ ዋላዎች ፡ ሆኑ ፤
ከሚያባርሩአቸው ፡ ፊት ፡ ተዳክመው ፡ ሄዱ ።

**፯፤** ዛይ ። ኢየሩሳሌም ፡ በጭንቀትዋና ፡ በመከራዋ ፡ ወራት ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ የነበረላትን ፡ የከበረን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አሰበች ፤
ሕዝብዋ ፡ በአስጨናቂዎች ፡ እጅ ፡ በወደቀ ፡ ጊዜ ፡ የሚረዳትም ፡ በሌላት ፡ ጊዜ ፥
አስጨናቂዎች ፡ አዩአት ፡ በመፍረስዋም ፡ ሳቁ ።

**፰፤** ሔት ። ኢየሩሳሌም ፡ እጅግ ፡ ኃጢአት ፡ ሠር ታለች ፤ ስለዚህ ፡ ረከሰለች ፤
ያከብሩአት ፡ የነበሩ ፡ ሁሉ ፡ ኀፍረተ ፡ ሥጋዋን ፡ አይተዋታልና ፡ አቃለሉአት ፤
እርስዋም ፡ እየጮኸች ፡ ታለቅሳለች ፡ ወደ ፡ ኋላም ፡ ዘወር ፡ አለች ።

**፱፤** ጤት ። አደፍዋ ፡ በልብስዋ ፡ ዘርፍ ፡ ነበረ ፤ ፍጻ ሜዋን ፡ አላሰበችም ፤
ስለዚህ ፡ በድንቅ ፡ ተዋርዳለች ፥ የሚያጽናና ትም ፡ የለም ፤
አቤቱ ፥ ጠላት ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎአልና ፡ መከ ራዬን ፡ ተመልከት ።

**፲፤** ዮድ ። አስጨናቂው ፡ በከበረ ፡ ነገርዋ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ ዘረጋ ፤
ወደ ፡ ጉባኤህ ፡ እንዳይገቡ ፡ ያዘዝሃቸው ፡ አሕ ዛብ ፡
ወደ ፡ መቅደስዋ ፡ ሲገቡ ፡ አይታለችና ።

**፲፩፤** ካፍ ። ሕዝብዋ ፡ ሁሉ ፡ እየጮኹ ፡ ያለቅሳሉ ፡ እንጀራም ፡ ይፈልጋሉ ፤
ሰውነታቸውን ፡ ለማበርታት ፡ የከበረ ፡ ሀብታ ቸውን ፡ ስለ ፡ መብል ፡ ሰጥተዋል ፤
አቤቱ ፥ ተጐሳቍያለሁና ፡ እይ ፥ ተመልከትም ።

**፲፪፤** ላሜድ ። እናንተ ፡ መንገድ ፡ አላፊዎች ፡ ሁሉ ፥ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ምንም ፡ የለምን ?
እግዚአብሔር ፡ በጽኑ ፡ ቍጣው ፡ ቀን ፡ እኔን ፡ እንዳስጨነቀበት ፡
በእኔ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተደረገው ፡ እንደ ፡ እኔ ፡ መከራ ፡ የሚመስል ፡ መከራ ፡ እንዳለ ፡ ተመ ልከቱ ፥ እዩ ።

**፲፫፤** ሜም ። ከላይ ፡ እሳትን ፡ ወደ ፡ አጥንቴ ፡ሰደደ ፡ በረታችበትም ፤
ለእግሬ ፡ ወጥመድ ፡ ዘረጋ ፡ ወደ ፡ ኋላም ፡ መለ ሰኝ ፥
አጠፋኝም ፡ ቀኑንም ፡ ሁሉ ፡ አደከመኝ ።

**፲፬፤** ኖን ። የኃጢአቶቼ ፡ ቀንበር ፡ በእጁ ፡ ተይዛለች ፤ ታስረው ፡ በአንገቴ ፡ ላይ ፡ ወጥተዋል ፤ ጕልበ ቴን ፡ አደከመ ።
ጌታ ፡ በፊታቸው ፡ እቆም ፡ ዘንድ ፡ በማልችላ ቸው ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠኝ ።

**፲፭፤** ሳምኬት ። ጌታ ፡ ኃያላኖቼን ፡ ሁሉ ፡ ከውስጤ ፡ አስወገዳቸው ፤
ጕልማሶቼን ፡ ያደቅቅ ፡ ዘንድ ፡ ጉባኤን ፡ ጠራ ብኝ ፤
ጌታ ፡ ድንግሊቱን ፡ የይሁዳን ፡ ልጅ ፡ በመጥመ ቂያ ፡ እንደሚረገጥ ፡ አድርጎ ፡ ረገጣት ።

**፲፮፤** ዔ ። የሚያጽናናኝ ፡ ነፍሴንም ፡ የሚያበረታት ፡ ከእኔ ፡ ርቆአልና ፡
ስለዚህ ፡ አለቅሳለሁ ፤ ዓይኔ ፥ ዓይኔ ፡ ውኃ ፡ ያፈ ስሳል ።
ጠላት ፡ በርትቶአልና ፡ ልጆቼ ፡ ጠፍተዋል ።

**፲፯፤** ፌ ። ጽዮን ፡ እጅዋን ፡ ዘረጋች ፤ የሚያጽናናት ፡ የለም ፤
እግዚአብሔር ፡ በያዕቆብ ፡ ዙሪያ ፡ ያሉትን ፡ እን ዲያስጨንቁት ፡ አዘዘ ፤
ኢየሩሳሌም ፡ በመካከላቸው ፡ እንደ ፡ ርኩስ ፡ ነገር ፡ ሆናለች ።

**፲፰፤** ጻዴ ። በአፉ ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ ዓመፅ ፡ አድርጌአለ ሁና ፡ እግዚአብሔር ፡ጻድቅ ፡ ነው ።
እናንተ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፥ እባካችሁ ፥ ስሙ ፡ መከራዬንም ፡ ተመልከቱ ፤
ደናግሎቼና ፡ ጕበዛዝቴ ፡ ተማርከው ፡ ሄዱ ።

**፲፱፤** ቆፍ ። ውሽሞቼን ፡ ጠራሁ ፡ እነርሱም ፡ አታለ ሉኝ ፤
ካህናቶቼና ፡ ሽማግሌዎቼ ፡ ሰውነታቸውን ፡ ያበረቱ ፡ ዘንድ ፡
መብል ፡ ሲፈልጉ ፡ በከተማ ፡ ውስጥ ፡ ሞቱ ።

**፳፤** ሬስ ። አቤቱ ፥ ተጨንቄአለሁና ፥ አንጀቴም ፡ ታውኮብኛልና ፡ ተመልከት ፤
ዓመፃን ፡ ፈጽሞ ፡ አድርጌአለሁና ፡ ልቤ ፡ በው ስጤ ፡ ተገላበጠብኝ ፤
በሜዳ ፡ ሰይፍ ፡ ልጆቼን ፡ አጠፋ ፡ በቤትም ፡ ሞት ፡ አለ ።

**፳፩፤** ሳን ። እኔ ፡ እየጮኽሁ ፡ እንደማለቅስ ፡ ሰምተ ዋል ፤ የሚያጽናናኝ ፡ የለም ፤
ጠላቶቼ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ መከራዬ ፡ ሰምተዋል ፤ አንተ ፡ አድርገኸዋልና ፡ ደስ ፡ አላቸው ፤
ስለ ፡ እርሱ ፡ የተናገርኸውን ፡ ቀን ፡ ታመጣለህ ፡ እነርሱም ፡ እንደ ፡ እኔ ፡ ይሆናሉ ።

**፳፪፤** ታው ። ልቅሶዬ ፡ እጅግ ፡ ነውና ፥ ልቤም ፡ ደክ ሞአልና ፡
ክፋታቸው ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ፊትህ ፡ ይድረስ ፥
ስለ ፡ ኃጢአቴ ፡ ሁሉ ፡ እንዳደረግህብኝ ፡ አድር ግባቸው ።

## ምዕራፍ፡፪።

፩፤ አሌፍ። ጌታ፡በቍጣው፡የጽዮንን፡ሴት፡ልጅ፡እንደ፡ምን፡አደመናት!
የእስራኤልን፡ውበት፡ከሰማይ፡ወደ፡ምድር፡ጣለ፤
በቍጣውም፡ቀን፡የእግሩን፡መረገጫ፡አላሰበም።

፪፤ ቤት። ጌታ፡የያዕቆብን፡ማደሪያዎች፡ሁሉ፡ዋጠ፤ አልራራምም፤
በመዓቱ፡የይሁዳን፡ሴት፡ልጅ፡አምቦች፡አፈረሰ፤
ወደ፡ምድርም፡አወረዳቸው፤ መንግሥቷንና፡አለቆችዋን፡አረከሰ።

፫፤ ጋሜል። በጽኑ፡ቍጣው፡የእስራኤልን፡ቀንድ፡ሁሉ፡ቀጠቀጠ፤
ቀኙ፡እጁን፡ከጠላት፡ፊት፡ወደ፡ኋላ፡መለሰ፤
በዙሪያውም፡እንደሚበላ፡እንደ፡እሳት፡ነበልባል፡ያዕቆብን፡አቃጠለ።

፬፤ ዳሌጥ። ቀስቱን፡እንደ፡ጠላት፡ገተረ፤ እንደ፡አስጨናቂ፡ቀኝ፡እጁን፡አጸና፤
ለዓይንም፡የሚያምረውን፡ሁሉ፡ገደለ፤
በጽዮን፡ሴት፡ልጅ፡ድንኳን፡መዓቱን፡እንደ፡እሳት፡አፈሰሰ።

፭፤ ሄ። ጌታ፡እንደ፡ጠላት፡ሆነ፤ እስራኤልን፡ዋጠ፤
አዳራሾችዋን፡ሁሉ፡ዋጠ፤ አምቦችዋን፡አጠፋ፤
በይሁዳም፡ሴት፡ልጅ፡ኀዘንና፡ልቅሶን፡አበዛ።

፮፤ ዋው። ማደሪያውን፡እንደ፡አትክልት፡ነቀለ፤ የበዓሉን፡ስፍራ፡አጠፋ፤
እግዚአብሔር፡በጽዮን፡ዓመት፡በዓሉንና፡ሰንበቱን፡አስረሳ፤
በቍጣውም፡መዓት፡ንጉሡንና፡ካህኑን፡አቃለለ።

፯፤ ዛይ። ጌታ፡መሠዊያውን፡ጣለ፤ መቅደሱን፡ጠላ፤
የአዳራሾችዋንም፡ቅጥር፡በጠላት፡እጅ፡አሳልፎ፡ሰጠ፤
ድምፃቸውን፡እንደ፡ዓመት፡በዓል፡ቀን፡በእግዚአብሔር፡ቤት፡ከፍ፡ከፍ፡አደረጉ።

፰፤ ሔት። እግዚአብሔር፡የጽዮንን፡ሴት፡ልጅ፡ቅጥር፡ያፈርስ፡ዘንድ፡አሰበ፤
የመለኪያውን፡ገመድ፡ዘረጋ፤ እጁን፡ከማጥፋት፡አልመለሰም፤
ምሽጉና፡ቅጥሩ፡እንዲያለቅሱ፡አደረገ፤ በአንድነት፡ደከሙ።

፱፤ ጤት። በሮችዋ፡በመሬት፡ውስጥ፡ሰጠሙ፤ መወርወሪያዎችዋን፡አጠፋ፡ሰበረም፤
ንጉሥዋና፡አለቆችዋ፡ሕግ፡በሌለባቸው፡በአሕዛብ፡መካከል፡ኾኑ፤
ነቢያቶችዋም፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ራእይ፡አላገኙም።

፲፤ ዮድ። የጽዮን፡ሴት፡ልጅ፡ሽማግሌዎች፡ዝም፡ብለው፡በመሬት፡ላይ፡ተቀምጠዋል፤
ትቢያን፡በራሳቸው፡ላይ፡ነሰነሱ፤ ማቅም፡ታጠቁ፤
የኢየሩሳሌም፡ደናግል፡ራሳቸውን፡ወደ፡ምድር፡አዘነበሉ።

፲፩፤ ካፍ። ሕፃኑና፡ጡት፡የሚጠባው፡በከተማይቱ፡ጐዳና፡ላይ፡ሲዝሉ፤
ዓይኔ፡በእንባ፡ደከመች፤ አንጀቴም፡ታወከ፤
ስለ፡ወገኔ፡ሴት፡ልጅ፡ቅጥቃጤ፡ጉበቴ፡በምድር፡ላይ፡ተዘረገፈ።

፲፪፤ ላሜድ። በከተማ፡ጐዳና፡እንደ፡ተወጋ፡ሰው፡በዛሉ፡ጊዜ፤
ነፍሳቸውም፡በእናቶቻቸው፡ብብት፡በወጣች፡ጊዜ፤
እናቶቻቸውን፦ እህልና፡የወይን፡ጠጅ፡ወዴት፡አለ? ይሉአቸዋል።

፲፫፤ ሜም። የኢየሩሳሌም፡ሴት፡ልጅ፡ሆይ፤ ምን፡እመሰክርልሻለሁ? በምንስ፡እመስልሻለሁ?
ድንግሊቱ፡የጽዮን፡ልጅ፡ሆይ፤ አጽናናሽ፡ዘንድ፡በምን፡አስተካክልሻለሁ?
ስብራትሽ፡እንደ፡ባሕር፡ታላቅ፡ነውና፤ የሚፈውስሽ፡ማን፡ነው?

፲፬፤ ኖን። ነቢያቶችሽ፡ከንቱና፡ሐሰተኛ፡ራእይ፡አይተውልሻል፤
ምርኮሽንም፡ይመልሱ፡ዘንድ፡በደልሽን፡አልገለጡም፤
ከንቱና፡የማይረባ፡ነገርንም፡አይተውልሻል።

፲፭፤ ሳምኬት። መንገድ፡አላፊዎች፡ሁሉ፡እጃቸውን፡ያጨበጭቡብሻል፤—
በውኑ፡የውበት፡ፍጻሜና፡የምድር፡ሁሉ፡ደስታ፡የሚሉአት፡ከተማ፡ይህች፡ናትን? እያሉ፤
በኢየሩሳሌም፡ሴት፡ልጅ፡ላይ፡ያፍዋጫሉ፤ ራሳቸውንም፡ያነቃንቃሉ።

፲፮፤ ዔ። ጠላቶችሽ፡ሁሉ፡አፋቸውን፡አላቀቁብሽ፤
እያፍዋጩና፡ጥርሳቸውን፡እያፋጩ፦ ውጠናታል፤
ነገር፡ግን፡ተስፋ፡ያደረግናት፡ቀን፡ይህች፡ናት፤ አግኝተናታል፡አይተናታል፡ይላሉ።

፲፯፤ ፌ። እግዚአብሔር፡ያሰበውን፡አደረገ፤ በቀድሞ፡ዘመን፡ያዘዘውን፡ቃል፡ፈጸመ፤
አፈረሰ፡አልራራምም፤
ጠላትንም፡ደስ፡አሰኘብሽ፤ የሚያስጨንቁሽንም፡ቀንድ፡ከፍ፡ከፍ፡አደረገ።

፲፰፤ ጻዴ። ልባቸው፡ወደ፡ጌታ፡ጮኸ፤
የጽዮን፡ሴት፡ልጅ፡ቅጥር፡ሆይ፤ እንባሽን፡እንደ፡ፈሳሽ፡ቀንና፡ሌሊት፡አፍስሺ፤
ለሰውነትሽ፡ዕረፍት፡አትስጪ፤ የዓይንሽ፡ብሌን፡አታቋርጥ።

፲፱፤ ቆፍ። ተነሺ፤ በሌሊት፡በመጀመሪያ፡ክፍል፡ጩኺ፤
በጌታም፡ፊት፡ልብሽን፡እንደ፡ውኃ፡አፍስሺ፤
በጐዳና፡ሁሉ፡ራስ፡ላይ፡በራብ፡ስለ፡ደከሙ፡ስለ፡ሕፃናትሽ፡ነፍስ፡እጆችሽን፡ወደ፡

እርሱ ፡ አንሺ ።

፳ ሬስ ። አቤቱ ÷ እይ ፤ በማን ፡ ላይ ፡ እንደዚህ ፡ እንዳደረግህ ፡ ተመልከት ።
በውኑ ፡ ሴቶች ፡ ፍሬያቸውን ÷ ያቀማጠሉአቸውን ፡ ሕፃናት ÷ ይበላሉን ?
በውኑ ፡ ካህኑና ፡ ነቢዩ ፡ በጌታ ፡ መቅደስ ፡ ውስጥ ፡ ይገደላሉን ?

፳፩ ሳን ። ብላቴናውና ፡ ሽማግሌው ፡ በመንገዶች ፡ ላይ ፡ ተጋደሙ ፤
ደናግሎቼና ፡ ጕበዛዝቴ ፡ በሰይፍ ፡ ወድቀዋል ፤
በቍጣህ ፡ ቀን ፡ ገደልሃቸው ፤ ሳትራራ ፡ አረድሃቸው ።

፳፪ ታው ። እንደ ፡ በዓል ፡ ቀን ፡ የሚያስፈሩኝን ፡ ከዙሪያዬ ፡ ጠራህ ÷
በእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ ቀንም ፡ ያመለጠ ፡ ወይም ፡ የቀረ ፡ አልተገኘም ፤
ያቀማጠልኋቸውንና ፡ ያሳደግኋቸውን ፡ ጠላቴ ፡ በላቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ አሌፍ ። በቍጣው ፡ በትር ፡ መከራ ፡ ያየ ፡ ሰው ፡ እኔ ፡ ነኝ ።
፪ ብርሃን ፡ ወደ ፡ ሌለበት ፡ ወደ ፡ ጨለማ ፡ መርቶ ፡ ወሰደኝ ።
፫ ዘወትር ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ እጁን ፡ በላዩ ፡ መለሰ ።
፬ ቤት ። ሥጋዬንና ፡ ቍርበቴን ፡ አስረጀ ÷ አጥንቴን ፡ ሰበረ ።
፭ ቅጥር ፡ ሠራብኝ ፡ በሐሞትና ፡ በድካምም ፡ ከበበኝ ።
፮ ቀድሞ ፡ ሞተው ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ በጨለማ ፡ አኖረኝ ።
፯ ጋሚል ። እንዳልወጣ ፡ በዙሪያዬ ፡ ቅጥር ፡ ሠራብኝ ፤ ሰንሰለቴን ፡ አከበደ ።
፰ በጠራሁና ፡ በጮኽሁ ፡ ጊዜ ፡ ጸሎቴን ፡ ከለከለ ።
፱ መንገዴን ፡ በተጠረበ ፡ ድንጋይ ፡ ዘጋ ÷ ጐዳናዬንም ፡ አጣመመ ።
፲ ዳሌጥ ። እንደሚሸምቅ ፡ ድብ ፡ እንደ ፡ ተሸሸገም ፡ አንበሳ ፡ ሆነብኝ ።
፲፩ መንገዴን ፡ ለወጠ ÷ ገነጣጠለኝም ፤ ብድማ ፡ አደረገኝ ።
፲፪ ቀስቱን ፡ ገተረ ፡ ለፍላጻውም ፡ እንደ ፡ ጊጤ ፡ አደረገኝ ።
፲፫ ሄ ። የሰገበውን ፡ ፍላጻዎች ፡ በኵላሊቴ ፡ ውስጥ ፡ ተከለ ።
፲፬ ለወገኔ ፡ ሁሉ ፡ ማላገጫ ፡ ቀኑንም ፡ ሁሉ ፡ መሰለቂያ ፡ ሆንሁ ።
፲፭ ምሬት ፡ ሞላብኝ ፡ በእሬትም ፡ አጠገበኝ ።
፲፮ ዋው ። ጥርሴን ፡ በጭንጫ ፡ ሰበረ ÷ በአመድም ፡ ከደነኝ ።
፲፯ ነፍሴን ፡ ከሰላም ፡ አራቅህ ፤ በጎ ፡ ነገርን ፡ ረሳሁ ።
፲፰ እኔም ፡— ኃይሌ ፡ ከእግዚአብሔርም ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡ ተስፋዬ ፡ ጠፋ ፡ አልሁ ።
፲፱ ዛይ ። መከራዬንና ፡ ችግሬን ፡ እሬትንና ፡ ሐሞትን ፡ አስብ ።
፳ ነፍሴ ፡ እያሰበችው ፡ በውስጧ ፡ ፈዘዘች ።
፳፩ ይህችን ፡ በልቤ ፡ አኖራለሁ ÷ ስለዚህ ፡ እታገሣለሁ ።
፳፪ ሔት ። ያልጠፋነው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ምሕረት ፡ የተነሣ ፡ ነው ፤ ርኅራኄው ፡ አያልቅምና ።
፳፫ ማለዳ ፡ ማለዳ ፡ አዲስ ፡ ነው ፤ ታማኝነትህ ፡ ብዙ ፡ ነው ።
፳፬ ነፍሴ ፡— እግዚአብሔር ፡ እድል ፡ ፈንታዬ ፡ ነው ፤ ስለዚህ ፡ ተስፋ ፡ አደርገዋለሁ ፡ አለች ።
፳፭ ጤት ። እግዚአብሔር ፡ በተስፋ ፡ ለሚጠብቁት ፡ ለምትሻውም ፡ ነፍስ ፡ መልካም ፡ ነው ።
፳፮ ሰው ፡ ዝም ፡ ብሎ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ማዳን ፡ ተስፋ ፡ ቢያደርግ ፡ መልካም ፡ ነው ።
፳፯ ሰው ፡ በታናሽነቱ ፡ ቀንበር ፡ ቢሸከም ፡ መልካም ፡ ነው ።
፳፰ ዮድ ። እርሱ ፡ አሸክሞታልና ፡ ዝም ፡ ብሎ ፡ ለብቻው ፡ ይቀመጥ ።
፳፱ ተስፋ ፡ የሆነው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አፉን ፡ በአፈር ፡ ውስጥ ፡ ያኑር ።
፴ ጕንጩን ፡ ለሚመታው ፡ ይስጥ ÷ ስድብንም ፡ ይጥገብ ።
፴፩ ካፍ ። ጌታ ፡ ለዘላለም ፡ አይጥልምና ፤
፴፪ ቢያሳዝንም ፡ እንደ ፡ ምሕረቱ ፡ ብዛት ፡ ይራራልና ፤
፴፫ የሰውን ፡ ልጆች ፡ ከልቡ ፡ አያስጨንቅም ÷ አያሳዝንምም ።
፴፬ ላሜድ ። በምድር ፡ የተጋዙትን ፡ ሁሉ ፡ ከእግሩ ፡ በታች ፡ ይረግጣቸው ፡ ዘንድ ÷
፴፭ የሰውን ፡ ፍርድ ፡ በልዑል ፡ ፊት ፡ ይመልስ ፡ ዘንድ ÷
፴፮ የሰውን ፡ ፍርድ ፡ ያጣምም ፡ ዘንድ ፡ ጌታ ፡ እሺ ፡ አይልም ።
፴፯ ሜም ። ጌታ ፡ ያላዘዘውን ፡ የሚልና ፡ የሚፈጽም ፡ ማን ፡ ነው ?
፴፰ ከልዑል ፡ አፍ ፡ ክፉና ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ አይወጣምን ?
፴፱ ሕያው ፡ ሰው ፡ የሚያጕረመርም ÷ ሰው ፡ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ ቅጣት ፡ የሚያጕረመርም ፡ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
፵ ኖን ። መንገዳችንን ፡ እንመርምርና ፡ እንፈትን ÷ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ እንመለስ ።
፵፩ ልባችንን ፡ ከእጃችን ፡ ጋር ፡ በሰማይ ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እናንሣ ።
፵፪ በድለናል ፡ ዐምፀናልም ÷ አንተም ፡ ይቅር ፡ አላልህም ።
፵፫ ሳምኬት ። በቍጣ ፡ ከደንኸን ፡ አሳደድኸንም ፤ ገደልኸን ÷ አልራራህም ።
፵፬ ጸሎት ፡ እንዳያልፍ ፡ ራስህን ፡ በደመና ፡ ከደንህ ።
፵፭ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ጕድፍና ፡ ውዳቂ ፡ አደረግኸን ።
፵፮ ዔ ። ጠላቶቻችን ፡ ሁሉ ፡ አፋቸውን ፡ አላቀቁብን ።
፵፯ ድንጋጤና ፡ ቍጣ ÷ ጥፋትና ፡ ቅጥቃጤ ፡ ሆነብን ።

፶፩ ስለ ፡ ወገኔ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ቅጥቃጤ ፡ ዓይኔ ፡ የውኃ ፡ ፈሳሽ ፡ አፈሰሰች ።

፶፱፣፶፩ ፌ ። እግዚአብሔር ፡ ከሰማይ ፡ እስኪጐበኝና ፡ እስኪመለከት ፡ ድረስ ፡
ዓይኔ ፡ ሳታቋርጥ ፡ ዝም ፡ ሳትል ፡ እንባ ፡ ታፈስ ሳለች ።

፶፩ ስለ ፡ ከተማዬ ፡ ቈነጃጅት ፡ ሁሉ ፡ ዓይኔ ፡ ነፍሴን ፡ አሳዘነች ።

፶፪ ጻዴ ። በከንቱ ፡ ነገር ፡ ጠላቶች ፡ የሆኑኝ ፡ እንደ ፡ ወፍ ፡ ማደንን ፡ አደኑኝ ።

፶፫ ሕይወቴን ፡ በጕድጓድ ፡ አጠፉ ÷ በላዬም ፡ ድንጋይ ፡ ጣሉ ።

፶፬ በራሴ ፡ ላይ ፡ ውኆች ፡ ተከነበሉ ፤ እኔም ፡— ጠፋሁ ፡ ብዬ ፡ ነበር ።

፶፭ ቆፍ ። አቤቱ ÷ በጠለቀ ፡ ጕድጓድ ፡ ውስጥ ፡ ሆኜ ፡ ስምህን ፡ ጠራሁ ።

፶፮ ድምፄን ፡ ሰማህ ፤ ጆሮህን ፡ ከልመናዬ ፡ አትመልስ ።

፶፯ በጠራሁህ ፡ ቀን ፡ ቀርበህ ፡— አትፍራ ፡ አልህ ።

፶፰ ሬስ ። ጌታ ፡ ሆይ ÷ ስለ ፡ ነፍሴ ፡ ተምዋግተህ ፡ ሕይወቴን ፡ ተቤዠህ ።

፶፱ አቤቱ ÷ ጭንቀቴን ፡ አይተሃል ÷ ፍርዴን ፡ ፍረድልኝ ።

፷ በቀላቸውን ፡ ሁሉና ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ አሳባቸውን ፡ ሁሉ ፡ አየህ ።

፷፩ ሳን ። አቤቱ ÷ ስድባቸውንና ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ አሳባቸውን ፡ ሁሉ ÷

፷፪ የተነሡብኝን ፡ ሰዎች ፡ ከንፈሮች ፡ ቀኑንም ፡ ሁሉ ፡ ያሰቡብኝን ፡ አሳባቸውን ፡ ሰማህ ።

፷፫ መቀመጣቸውንና ፡ መነሣታቸውን ፡ ተመልከት ፤ እኔ ፡ መሳለቂያቸው ፡ ነኝ ።

፷፬ ታው ። አቤቱ ÷ እንደ ፡ እጃቸው ፡ ሥራ ፡ ፍዳቸውን ፡ ትከፍላቸዋለህ ።

፷፭ የልብ ፡ ዕውርነትንና ፡ እርግማንህን ፡ ትሰጣቸዋለህ ።

፷፮ አቤቱ ÷ በቍጣ ፡ ታሳድዳቸዋለህ ፡ ከሰማይም ፡ በታች ፡ ታጠፋቸዋለህ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ አሌፍ ። ወርቁ ፡ እንዴት ፡ ደበሰ ! ጥሩው ፡ ወርቅ ፡ እንዴት ፡ ተለወጠ !
የመቅደሱ ፡ ድንጋዮች ፡ በጐዳና ፡ ሁሉ ፡ ራስ ፡ ተበተኑ ።

፪ ቤት ። ጥሩ ፡ ወርቅ ፡ የሚመስሉ ፡ የከበሩ ፡ የጽዮን ፡ ልጆች ÷
የሸክላ ፡ ሠሪ ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ሠራው ፡ እንደ ፡ ሸክላ ፡ ዕቃ ፡ እንዴት ፡ ተቈጠሩ !

፫ ጋሜል ። ቀበሮች ፡ እንኳ ፡ ጡታቸውን ፡ ገልጠው ፡ ግልገሎቻቸውን ፡ አጠቡ ፤
የወገኔ ፡ ልጅ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሰጐን ፡ ጨካኝ ፡ ሆነች ።

፬ ዳሌጥ ። ጡት ፡ የሚጠባው ፡ የሕፃን ፡ ምላስ ፡ ከጥም ፡ የተነሣ ፡ ወደ ፡ ትናጋው ፡ ተጣበቀ ፤
ሕፃናት ፡ እንጀራ ፡ ለመኑ ÷ የሚቈርስላቸውም ፡ የለም ።

፭ ሄ ። የጣፈጠ ፡ ነገር ፡ ይበሉ ፡ የነበሩ ፡ በመንገድ ፡ ጠፉ ፤
በቀይ ፡ ግምጃ ፡ ያድጉ ፡ የነበሩ ፡ የፍግ ፡ ክምር ፡ አቀፉ ።

፮ ዋው ። የማንም ፡ እጅ ፡ ሳይወድቅባት ፡ ድንገት ፡ ከተገለበጠች ፡
ከሰዶም ፡ ኃጢአት ፡ ይልቅ ፡ የወገኔ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ኃጢአት ፡ በዛች ።

፯ ዛይ ። አለቆችዋ ፡ ከበረዶ ፡ ይልቅ ፡ ጥሩ ÷ ከወተት ፡ ይልቅ ፡ ነጭ ፡ ነበሩ ፤
ገላቸው ፡ ከቀይ ፡ ዕንቍ ፡ ይልቅ ፡ ቀይ ፡ ነበረ ÷ መልካቸውም ፡ እንደ ፡ ሰንፔር ፡ ነበረ ።

፰ ሔት ። ፊታቸው ፡ ከጥቀርሻ ፡ ይልቅ ፡ ጠቍሮአል ÷ በመንገድም ፡ አልታወቁም ፤
ቍርበታቸው ፡ ወደ ፡ አጥንታቸው ፡ ተጣብቆአል ፤ ደርቆአል ፤ እንደ ፡ እንጨት ፡ ሆኖአል ።

፱ ጤት ። በሰይፍ ፡ የሞቱ ፡ በራብ ፡ ከሞቱት ፡ ይሻላሉ ፤
እነዚህ ፡ የምድርን ፡ ፍሬ ፡ አጥተው ፡ ተወግተውም ፡ ቀጥነዋል ።

፲ ዮድ ። የርኅሩኆች ፡ ሴቶች ፡ እጆች ፡ ልጆቻቸውን ፡ ቀቅለዋል ፤
የወገኔ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ በመቀጥቀጥዋ ፡ መብል ፡ ሆኑአቸው ።

፲፩ ካፍ ። እግዚአብሔር ፡ መዓቱን ፡ ፈጽሞአል ÷ጽኑ ፡ ቍጣውን ፡ አፍስሶአል ፤
እሳትን ፡ በጽዮን ፡ ውስጥ ፡ አቃጠለ ÷ መሠረትዋንም ፡ በላች ።

፲፪ ላሜድ ። የምድር ፡ ነገሥታት ፡ በዓለምም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡
አስጨናቂና ፡ ጠላት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በር ፡ እንዲገባ ፡ አላመኑም ።

፲፫ ሜም ። የጻድቃንን ፡ ደም ፡ በውስጥዋ ፡ ስላፈሰሱ ፡
ስለ ፡ ነቢያቶችዋ ፡ ኃጢአትና ፡ ስለ ፡ ካህናቶች ፡ በደል ፡ ነው ።

፲፬ ኖን ። ታውረው ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ ተቅበዘበዙ ፤
ልብሳቸው ፡ እንዳይዳሰስ ፡ በደም ፡ ረክሰዋል ።

፲፭ ሳምኬት ። እናንተ ፡ ርኩሳን ÷ ራቁ ÷ ርቃችሁም ፡ሂዱ ÷ አትንኩ ፡ ብለው ፡ጮኹባቸው ።
በሸሹና ፡ በተቅበዘበዙ ፡ ጊዜ ÷ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡— በዚህ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አይኖሩም ፡ ተባለ ።

፲፮ ፌ ። የእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በተናቸው ፡ እርሱም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አይመለከታቸውም ፤
የካህናቱን ፡ ፊት ፡ አላፈሩም ÷ ሽማግሌዎቹንም ፡ አላከበሩም ።

፲፯ ፌ ። ዓይናችን ፡ ወደ ፡ ከንቱ ፡ ረዳታችን ፡ ገና ፡ ሲመለከት ፡ ጠፍቶአል ፤
በመቆየታችን ፡ ማዳን ፡ የማይቻለውን ፡ ሕዝብ ፡ ጠብቀናል ።

፲፰ ጻዴ ። በአደባባያችን ፡ እንዳንሄድ ፡ ፍለጋች

ንን፡ተከተሉ፤
ፍጻሜያችን፡ቀርቦአል ፥ ዕድሜያችን፡አልቆ
አል ፥ ፍጻሜያችን፡ደርሶአል ።

፲፱፤ ቆፍ ። አሳዳጆቻችን፡ከሰማይ፡ንስር፡ይልቅ፡
ፈጣኖች፡ሆኑ፤
በተራሮች፡ላይ፡አሳደዱን ፥ በምድረ፡በዳ፡
ሸመቁብን ።

፳፤ ሬስ ። ስለ፡እርሱ፡— በአሕዛብ፡መካከል፡በጥ
ላው፡በሕይወት፡እንኖራለን፡ያልነው፡
በእግዚአብሔር፡የተቀባ ፥ የሕይወታችን፡እስ
ትንፋስ ፥ በጕድጓዳቸው፡ተያዘ ።

፳፩፤ ሳን ። በዖፅ፡ምድር፡የምትኖሪ፡የኤዶምያስ፡
ልጅ፡ሆይ ፥ ደስ፡ይበልሽ፡ሐሤትም፡አድ
ርጊ፤
ጽዋው፡ደግሞ፡ወደ፡አንቺ፡ያልፋል ፥ አን
ቺም፡ትሰክሪአለሽ፡ትራቈቻለሽም ።

፳፪፤ ታው ። የጽዮን፡ልጅ፡ሆይ ፥ የበደልሽ፡ቅጣት፡
ተፈጸመ፤ ከእንግዲህ፡ወዲህ፡አያስማርክ
ሽም ።
የኤዶምያስ፡ልጅ፡ሆይ ፥ በደልሽን፡ይቀጣል፤
ኃጢአትሽን፡ይገልጣል ።

## ምዕራፍ፡፭ ።

፩፤ አቤቱ ፥ የሆነብንን፡አስብ፤
ተመልከት፡ስድባችንንም፡እይ ።

፪፤ ርስታችን፡ለእንግዶች ፥
ቤቶቻችን፡ለሌሎች፡ሆኑ ።

፫፤ ድሀ፡አደጎችና፡አባት፡የሌለን፡ሆንናል፤
እናቶቻችን፡እንደ፡መበለቶች፡ሆነዋል ።

፬፤ ውኃችንን፡በብር፡ጠጣን፡
እንጨታችንን፡በዋጋ፡ገዛን ።

፭፤ አሳዳጆቻችን፡በአንገታችን፡ላይ፡ናቸው፤
እኛ፡ደከመናል፡ዕረፍትም፡የለንም ።

፮፤ ለግብጻውያንና፡ለአሦራውያን፡
እንጀራ፡እንጠግብ፡ዘንድ፡እጅ፡ሰጠን ።

፯፤ አባቶቻችን፡ኃጢአትን፡ሠሩ፡ዛሬም፡የሉም፤
እኛም፡በደላቸውን፡ተሸከምን ።

፰፤ ባሪያዎች፡ሠልጥነውብናል፤
ከእጃቸው፡የሚታደገን፡የለም ።

፱፤ ከምድረ፡በዳ፡ሰይፍ፡የተነሣ፡
በሕይወታችን፡እንጀራችንን፡እናመጣለን ።

፲፤ ከሚያቃጥል፡ከራብ፡ትኩሳት፡የተነሣ፡
ቁርበታችን፡እንደ፡ምድጃ፡ጠቈረ ።

፲፩፤ በጽዮን፡ሴቶችን ፥
በይሁዳም፡ከተሞች፡ደናግልን፡አጐሰቈሉ ።

፲፪፤ አለቆች፡በእጃቸው፡ተሰቀሉ፤
የሽማግሌዎች፡ፊት፡አልታፈረም ።

፲፫፤ ጕልማሶች፡ወፍጮን፡ተሸከሙ ፥
ልጆችም፡ከእንጨት፡በታች፡ተሰናከሉ ።

፲፬፤ ሽማግሌዎች፡ከአደባባይ ፥
ጕልማሶችም፡ከበገናቸው፡ተሻሩ ።

፲፭፤ የልባችን፡ደስታ፡ቀርቶአል፤
ዘፈናችን፡ወደ፡ልቅሶ፡ተለውጦአል ።

፲፮፤ አክሊል፡ከራሳችን፡ወድቆአል፤
ኃጢአት፡ሠርተናልና፡ወዮልን !

፲፯፤ ስለዚህ፡ልባችን፡ታምሞአል፤
ስለዚህም፡ነገር፡ዓይናችን፡ፈዝዞአል፤

፲፰፤ ስለ፡ጽዮን፡ተራራ ፥ ባድማ፡ሆናለችና ፥
ቀበሮችም፡ተመላልሰውባታልና ።

፲፱፤ አቤቱ ፥ አንተ፡ለዘላለም፡ትኖራለህ፤
ዙፋንህ፡ከትውልድ፡እስከ፡ትውልድ፡ነው ።

፳፤ ስለ፡ምን፡ለዘላለም፡ትረሳናለህ ?
ስለ፡ምንስ፡ለረጅም፡ዘመን፡ትተወናለህ ?

፳፩፤ አቤቱ ፥ ወደ፡አንተ፡መልሰን፡እኛም፡እንመ
ለሳለን፤
ዘመናችንን፡እንደ፡ቀድሞ፡አድስ ።

፳፪፤ ነገር፡ግን፡ፈጽመህ፡ጥለኸናል፤
እጅግ፡ተቈጥተኸናል ።

# ትንቢተ ፡ ሕዝቅኤል ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ በሠላሳኛው ፡ ዓመት ፡ በአራተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአምስተኛው ፡ ቀን ፡ በኮቦር ፡ ወንዝ ፡ በምርኮኞች ፡ መካከል ፡ ሳለሁ ፡ ሰማያት ፡ ተከፈቱ ፥ የእግዚአብሔርንም ፡ ራእይ ፡ አየሁ ። ፪ ንጉሡ ፡ ዮአኪን ፡ በተማረከ ፡ በአምስተኛው ፡ ፫ ዓመት ፡ ከወሩም ፡ በአምስተኛው ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በከለዳውያን ፡ አገር ፡ በኮቦር ፡ ወንዝ ፡ ወደ ፡ ቡዝ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ካህኑ ፡ ወደ ፡ ሕዝቅኤል ፡ መጣ ። የእግዚአብሔርም ፡ ፬ እጅ ፡ በዚያ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ሆነች ፥ እኔም ፤ አየሁ ፥ እነሆም ፥ ከሰሜን ፡ በኩል ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስና ፡ ታላቅ ፡ ደመና ፡ የሚበርቅም ፡ እሳት ፡ መጣ ፥ በዙሪያውም ፡ ፀዳል ፡ ነበረ ፥ በመካከልም ፡ በእሳቱ ፡ ውስጥ ፡ እንደሚብለጨለጭ ፡ የወርቅ ፡ ፭ ምስያ ፡ ነበረ ። ከመካከልም ፡ የአራት ፡ እንስሶች ፡ አምሳያ ፡ ወጣ ። መልካቸውም ፡ እንደ ፮ ዚህ ፡ ነበረ ፥ ሰውም ፡ ይመስሉ ፡ ነበር ። ለእያንዳንዱም ፡ አራት ፡ አራት ፡ ፊት ፥ ለእያንዳን ፯ ዱም ፡ አራት ፡ አራት ፡ ክንፍ ፡ ነበሩት ። እግሮቻቸውም ፡ ቀጥ ፡ ያሉ ፡ እግሮች ፡ ነበሩ ፤ የእግራቸውም ፡ ኰቴ ፡ እንደ ፡ ጥጃ ፡ እግር ፡ ኰቴ ፡ ነበረ ፤ እንደ ፡ ተወለወለ ፡ ናስም ፡ ይብለጨለጭ ፡ ፰ ነበር ። በክንፎቻቸውም ፡ በታች ፡ በእያራቱ ፡ ጐድናቸው ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ ነበረ ፤ ለአራቱም ፡ እንደዚህ ፡ ያሉ ፡ ፊትና ፡ ክንፍ ፡ ነበሩአ ፱ ቸው ። ክንፎቻቸው ፡ እርስ ፡ በእርሱ ፡ የተያያዘ ፡ ነበረ ፤ ሲሄዱም ፡ አይገላመጡም ፡ ነበር ፥ እያንዳንዱም ፡ ፊቱን ፡ አቅንቶ ፡ ይሄድ ፡ ነበር ። ፲ የፊታቸው ፡ አምሳያ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ፊት ፡ ነበረ ፥ ለአራቱም ፡ በስተ ፡ ቀኛቸው ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ፊት ፥ በስተ ፡ ግራቸውም ፡ እንደ ፡ ላም ፡ ፊት ፡ ነበራቸው ፥ ለአራቱም ፡ ደግሞ ፡ የንስር ፡ ፊት ፡ ነበራቸው ። ፲፩ ክንፋቸውም ፡ በላይ ፡ ተዘርግቶ ፡ ነበር ፥ የእያንዳንዱም ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ ክንፋቸው ፡ የተያያዙ ፡ ነበሩ ፥ ሁለት ፡ ሁለቱም ፡ ገላቸውን ፡ ይከድኑ ፡ ነበር ። ፲፪ እያንዳንዱም ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ቀጥ ፡ ብሎ ፡ ይሄድ ፡ ነበር ፤ መንፈስም ፡ ወደሚሄድበት ፡ ሁሉ ፡ ይሄዱ ፡ ነበር ፥ ሲሄዱም ፡ አይገላመጡም ፡ ነበር ። ፲፫ በእንስሶቹ ፡ መካከል ፡ እንደሚነድድ ፡ የእሳት ፡ ፍም ፡ ያለ ፡ ምስያ ፡ ነበረ ፤ በእንስሶች ፡ መካከል ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ የሚሄድ ፡ እንደ ፡ ፋና ፡ ያለ ፡ ምስያ ፡ ነበረ ፤ ለእሳቱም ፡ ፀዳል ፡ ነበረው ፥ ከእሳቱም ፡ መብረቅ ፡ ይወጣ ፡ ነበር ። ፲፬ እንስሶቹም ፡ እንደ ፡ መብረቅ ፡ ምስያ ፡ ይሮጡና ፡ ይመለሱ ፡ ነበር ።

፲፭ እንስሶችንም ፡ ስመለከት ፥ እነሆ ፥ በአራቱ ፡ እንስሶች ፡ አጠገብ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ መንኰራኵር ፡ አየሁ ። ፲፮ የመንኰራኵሩም ፡ መልክ ፡ እንደ ፡ ቢረሌ ፡ ነበረ ፤ አራቱም ፡ አንድ ፡ አምሳያ ፡ ነበሩ ፤ ሥራቸውም ፡ በመንኰራኵር ፡ ውስጥ ፡ እንዳለ ፡ መንኰራኵር ፡ ነበረ ። ፲፯ በእያራቱ ፡ ጐድናቸው ፡ ይሄዱ ፡ ነበር ፤ ሲሄዱም ፡ አይገላመጡም ፡ ነበር ። ፲፰ ቁመታቸውም ፡ የረዘመና ፡ የሚያስፈራ ፡ ነበረ ፤ የአራቱም ፡ ክበብ ፡ ዙሪያው ፡ በዓይን ፡ ተሞልቶ ፡ ነበር ። ፲፱ እንስሶቹም ፡ በሄዱ ፡ ጊዜ ፡ መንኰራኵሮቹ ፡ በአጠገባቸው ፡ ሄዱ ። እንስሶቹም ፡ ከምድር ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ባሉ ፡ ጊዜ ፡ መንኰራኵሮቹ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አሉ ። ፳ መንፈሱ ፡ ወደሚሄድበት ፡ ሁሉ ፡ እነርሱ ፡ ሄዱ ፤ የእንስሶች ፡ መንፈስ ፡

በመንኰራኵሮቹ፡ውስጥ፡ነበረና፡መንኰራኵ
ሮቹ፡በእነርሱ፡አጠገብ፡ከፍ፡ከፍ፡አሉ።
፳፩፤ የእንስሶች፡መንፈስ፡በመንኰራኵሮቹ፡ውስጥ፡
ነበረና፡እነዚያ፡ሲሄዱ፡እነዚህ፡ይሄዱ፡ነበር፤
እነዚያም፡ሲቆሙ፡እነዚህ፡ይቆሙ፡ነበር፤
እነዚያም፡ከምድር፡ከፍ፡ከፍ፡ሲሉ፡መንኰራኵ
ሮቹ፡በአጠገባቸው፡ከፍ፡ከፍ፡ይሉ፡ነበር።
፳፪፤ ከእንስሶች፡ራስ፡በላይ፡የሚያስፈራ፡በረዶ፡
የሚመስል፡የጠፈር፡አምሳያ፡በራሳቸው፡
፳፫፤ ላይ፡ተዘርግቶ፡ነበር። ከጠፈሩም፡በታች፡
ክንፎቻቸው፡እርስ፡በርሳቸው፡ተቃንተው፡
ነበር፤ለእያንዳንዱም፡ገላውን፡የሚከድኑ፡
፳፬፤ ሁለት፡ሁለት፡ክንፎች፡ነበሩት። ሲሄዱም፡
የክንፎቻቸው፡ድምፅ፡እንደ፡ብዙ፡ውኃ፡
ድምፅ፥እንደ፡ሁሉን፡የሚችል፡የአምላክም፡
ድምፅ፥እንደ፡ታላቅም፡ሠራዊት፡ድምፅ፡
ሆኖ፡ሰማሁ፤ሲቆሙም፡ክንፎቻቸውን፡ዝቅ፡
፳፭፤ ያደርጉ፡ነበር። በራሳቸውም፡ላይ፡ካለው፡
ጠፈር፡በላይ፡ድምፅ፡ተሰማ፤ ሲቆሙም፡
ክንፎቻቸውን፡ዝቅ፡ያደርጉ፡ነበር።
፳፮፤ በራሳቸውም፡በላይ፡ካለው፡ጠፈር፡በላይ፡
የሰንፔር፡ድንጋይ፡የሚመስል፡የዙፋን፡አም
ሳያ፡ነበረ፤በዙፋኑም፡አምሳያ፡ላይ፡እንደ፡
፳፯፤ ሰው፡መልክ፡አምሳያ፡ነበረ። ከወገቡም፡
አምሳያ፡ወደ፡ላይ፡የሚብለጨለጭ፡የወርቅ፡
ምስያ፡አየሁ፤ከወገቡም፡አምሳያ፡ወደ፡ታች፡
እንደ፡እሳት፡ምስያ፡አየሁ፤ በዙሪያውም፡
፳፰፤ ፀዳል፡ነበረ። በዝናብ፡ቀን፡በደመና፡ውስጥ፡
እንደ፡ቀስተ፡ደመና፡አምሳያ፥እንዲሁ፡
በዙሪያው፡ያለ፡ፀዳል፡አምሳያ፡ነበረ። የእ
ግዚአብሔር፡ክብር፡ምሳሌ፡መልክ፡ይህ፡
ነበረ። በየሁም፡ጊዜ፡በግምባሬ፡ተደፋሁ፥
የሚናገርንም፡ድምፅ፡ሰማሁ።

## ምዕራፍ፡፪።

፩፤ እርሱም፡— የሰው፡ልጅ፡ሆይ፥በእግርህ፡
፪፤ ቁም፡እኔም፡እናገርሃለሁ፡አለኝ። በተናገረ
ኝም፡ጊዜ፡መንፈስ፡ገባብኝ፡በእግሬም፡
፫፤ አቆመኝ፥የሚናገረኝንም፡ሰማሁ። እርሱም፡
እንዲህ፡አለኝ፡— የሰው፡ልጅ፡ሆይ፥በእኔ፡
ላይ፡ወደ፡ዐመፁ፡ወደ፡ዓመፀኞች፡ሰዎች፡
ወደ፡እስራኤል፡ልጆች፡እልክሃለሁ። እነር
ሱና፡አባቶቻቸው፡እስከ፡ዛሬ፡ድረስ፡ዐመ
፬፤ ፁብኝ። እነርሱ፡ፊታቸው፡የተጨማተረ፡
ልባቸውም፡የደነደነ፡ልጆች፡ናቸው። እኔ፡
ወደ፡እነርሱ፡እልክሃለሁ፤አንተም፡— ጌታ፡
እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡በላቸው።
፭፤ እነርሱም፡ዓመፀኛ፡ቤት፡ናቸውና፡ቢሰሙ፡
ወይም፡ባይሰሙ፡ነቢይ፡በመካከላቸው፡እን
፮፤ ዳለ፡ያውቃሉ። አንተ፥የሰው፡ልጅ፡ሆይ፥
ኵርንችትና፡እሾህ፡ከአንተ፡ጋር፡ቢኖሩም፥
አንተም፡በጊንጦች፡መካከል፡ብትቀመጥም፥
አትፍራቸው፥ቃላቸውንም፡አትፍራ፤አንተ፡
ቃላቸውን፡አትፍራ፥ከፊታቸውም፡የተነሣ፡
አትደንግጥ፤እነርሱ፡ዓመፀኛ፡ቤት፡ናቸውና።
፯፤ እነርሱ፡ዓመፀኛ፡ቤት፡ናቸውና፡ቢሰሙ፡
ወይም፡ባይሰሙ፡ቃሌን፡ትነግራቸዋለህ።
፰፤ አንተ፡ግን፥የሰው፡ልጅ፡ሆይ፥የምነግ
ርህን፡ስማ፤እንደዚያ፡እንደ፡ዓመፀኛው፡
ቤት፡ዓመፀኛ፡አትሁን፤አፍህን፡ክፈት፡የም
ሰጥህንም፡ብላ። ባየሁም፡ጊዜ፥እነሆ፡እጅ፡
፱፤ ወደ፡እኔ፡ተዘርግታ፡ነበር፤እነሆም፥የመጽ
፲፤ ሐፍ፡ጥቅልል፡ነበረበት። በፊቴም፡ዘረጋው፥
በውስጥና፡በውጭም፡ተጽፎበት፡ነበር፤ልቅ
ሶና፡ኀዘን፡ዋይታም፡ተጽፎበት፡ነበር።

## ምዕራፍ፡፫።

፩፤ እርሱም፡— የሰው፡ልጅ፡ሆይ፥ያገኘኸ
ውን፡ብላ፤ይህን፡መጽሐፍ፡ብላ፥ሄደህም፡
፪፤ ለእስራኤል፡ቤት፡ተናገር፡አለኝ። አፌንም፡
፫፤ ከፈትሁ፡መጽሐፉንም፡አጐረሰኝ። እርሱም፡—
የሰው፡ልጅ፡ሆይ፥አፍህ፡ይብላ፥በምሰጥ
ህም፡በዚህ፡መጽሐፍ፡ሆድህን፡ሙላ፡አለኝ።
እኔም፡በላሁት፥በአፌም፡ውስጥ፡እንደ፡
ማር፡ጣፈጠ።
፬፤ እንዲህም፡አለኝ፡— የሰው፡ልጅ፡ሆይ፥
ተነሥተህ፡ወደ፡እስራኤል፡ቤት፡ሂድ፥
፭፤ ቃሌንም፡ተናገራቸው። ወደ፡እስራኤል፡
ቤት፡እንጂ፡ንግግራቸው፡ወደ፡ጠለቀው፡
ቋንቋቸውም፡ወደማይታወቅ፡ሕዝብ፡አልተ
፮፤ ላክህምና፤ንግግራቸው፡ወደ፡ጠለቀው፡ቋን
ቋቸውም፡ወደማይታወቅ፡ቃላቸውንም፡
ታውቅ፡ዘንድ፡ወደማይቻልህ፡ሕዝብ፡አል
ላክሁህም። ወደ፡እነዚያስ፡ልኬህ፡ቢሆን፡
፯፤ ኖሮ፡በሰሙህ፡ነበር። ነገር፡ግን፡የእስራ
ኤል፡ቤት፡ሁሉ፡የጠነከረ፡ግምባርና፡የደነ
ደነ፡ልብ፡አላቸውና፥እኔንም፡መስማት፡
እንቢ፡ብለዋልና፡የእስራኤል፡ቤት፡አንተን፡
፰፤ አይሰሙም። እነሆ፥ፊትህን፡በፊታቸው፡
ግምባርህንም፡በግምባራቸው፡አጠንክሬአ
፱፤ ለሁ። ከቡላድ፡ድንጋይ፡ይልቅ፡እንዳለ፡
አልማዝ፡ግምባርህን፡አጠንክሬአለሁ፤እነ
ርሱ፡ዓመፀኛ፡ቤት፡ቢሆኑ፡አትፍራቸው፤
ከፊታቸውም፡የተነሣ፡አትደንግጥ።
፲፤ እርሱም፡— የሰው፡ልጅ፡ሆይ፥የነገርሁ
ህን፡ቃሌን፡ሁሉ፡በልብህ፡ተቀበል፡በጆሮ
፲፩፤ ህም፡ስማ። ተነሥተህም፡ወደ፡ተማረኩ፡
ወደ፡ወገንህ፡ልጆች፡ሂድ፤እነርሱም፡ቢሰሙ፡
ወይም፡ባይሰሙ፡— ጌታ፡እግዚአብሔር፡እን
ዲህ፡ይላል፡ብለህ፡ንገራቸው፡አለኝ።
፲፪፤ መንፈስም፡አነሣኝ፥በኋላዬም፡— የእግዚአ
ብሔር፡ክብር፡ከቦታው፡ይበረክ፡የሚል፡የጽኑ፡
፲፫፤ ንውጥውጥታ፡ድምፅ፡ሰማሁ። የአራቱም፡እን
ስሳ፡ክንፎች፡እርስ፡በርሳቸው፡ሲማቱ፥በአ
ጠገባቸውም፡የመንኰራኵሮችን፡ድምፅ፥
የጽኑውንም፡ንውጥውጥታ፡ድምፅ፡ሰማሁ።
፲፬፤ መንፈስ፡አንሥቶ፡አስወገደኝ፥እኔም፡በምሬ
ትና፡በመንፈሴ፡ሙቀት፡ሄድሁ፥የእግዚአብ

፲፭ ሔርም ፡ እጅ ፡ በላዬ ፡ በርትታ ፡ ነበር ። በቴልአቢብም ፡ ወዳሉ ፡ በኮቦርም ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ ወደ ፡ ተቀመጡ ፡ ምርኮኞች ፡ መጣሁ ፥ በተቀመጡበትም ፡ በታ ፡ ተቀመጥሁ ፤ በዚያም ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በድንጋጤ ፡ በመካከላቸው ፡ ተቀመጥሁ ።

፲፮ ከሰባቱም ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፲፯ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ ጠባቂ ፡ አድርጌሃለሁ ፤ ስለዚህ ፡ የአፌን ፡ ቃል ፡ ስማ ፡ ከእ ፲፰ ኔም ፡ ዘንድ ፡ አስጠንቅቃቸው ። እኔ ፡ ኃጢአተኛውን ፦ በእርግጥ ፡ ትሞታለህ ፡ በልሁት ፡ ጊዜ ፥ አንተም ፡ ባታስጠንቅቀው ፡ ነፍሱም ፡ እንድትድን ፡ ከክፉ ፡ መንገዱ ፡ ይመለስ ፡ ዘንድ ፡ ለኃጢአተኛው ፡ አስጠንቅቀህ ፡ ባትነግረው ፥ ያ ፡ ኃጢአተኛ ፡ በኃጢአት ፡ ይሞታል ፤ ደሙን ፡ ፲፱ ግን ፡ ከእጅህ ፡ እፈልጋለሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ አንተ ፡ ኃጢአተኛውን ፡ ብታስጠንቅቅ ፡ እርሱም ፡ ከኃጢአቱና ፡ ከክፉ ፡ መንገዱ ፡ ባይመለስ ፥ በኃጢአቱ ፡ ይሞታል ፥ አንተ ፡ ግን ፡ ነፍስህን ፡ ፳ አድነሃል ። ደግሞ ፡ ጻድቁ ፡ ከጽድቁ ፡ ተመልሶ ፡ ኃጢአት ፡ በሠራ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ በፊቱም ፡ ዕንቅፋትን ፡ ሳደርግ ፥ እርሱ ፡ ይሞታል ፤ አንተም ፡ አላስጠነቀቅኸውምና ፡ በኃጢአቱ ፡ ይሞታል ፡ ያደረጋትም ፡ ጽድቅ ፡ ነገር ፡ አትታሰብለትም ፤ ደሙን ፡ ግን ፡ ከእጅህ ፡ እፈልጋለሁ ። ፳፩ ነገር ፡ ግን ፡ ኃጢአት ፡ እንዳይሠራ ፡ ጻድቁን ፡ ብታስጠንቅቅ ፡ እርሱም ፡ ኃጢአት ፡ ባይሠራ ፥ ተጠንቅቆአልና ፡ በእርግጥ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራል ፤ አንተም ፡ ነፍስህን ፡ አድነሃል ።

፳፪ በዚያም ፡ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ነበረች ፥ እርሱም ፦ ተነሥተህ ፡ ወደ ፡ ቈላው ፡ ፳፫ ሂድ ፡ በዚያም ፡ እናገርሃለሁ ፡ አለኝ ። እኔም ፡ ተነሥቼ ፡ ወደ ፡ ቈላው ፡ ሄድሁ ፤ እነሆም ፥ በኮቦር ፡ ወንዝ ፡ እንዳየሁት ፡ ክብር ፡ ያለ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ በዚያ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፥ በግ ፳፬ ምባሬም ፡ ተደፋሁ ። መንፈስም ፡ ገባብኝ ፡ በእግሬም ፡ አቆመኝ ፥ ተናገረኝም ፡ እንዲህም ፡ ፳፭ አለኝ ፦ ሂድ ፥ ገብተህ ፡ ቤትህን ፡ ዝጋ ። አንተም ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ እነሆ ፥ ገመድ ፡ ያደርጉብሃል ፡ ያስሩህማል ፥ አንተም ፡ በመካ ፳፮ ከላቸው ፡ አትወጣም ፤ እኔም ፡ ምላስህን ፡ ከትናጋህ ፡ ጋር ፡ አጣብቃታለሁ ፡ አንተም ፡ ዲዳ ፡ ትሆናለህ ፥ እነርሱም ፡ ዓመፀኛ ፡ ቤት ፡ ናቸውና ፡ የሚዘልፍ ፡ ሰው ፡ አትሆንባቸውም ። ፳፯ ነገር ፡ ግን ፡ በተናገርሁህ ፡ ጊዜ ፡ አፍህን ፡ እከፍታለሁ ፥ እነርሱም ፡ ዓመፀኛ ፡ ቤት ፡ ናቸውና ፡ አንተ ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ የሚሰማ ፡ ይስማ ፥ የማይሰማም ፡ አይስማ ፡ ትላቸዋለህ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ አንተም ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ጡብን ፡ ወስደህ ፡ በፊትህ ፡ አኑራት ፡ የኢየሩሳሌምንም ፡ ፪ ከተማ ፡ ስዕል ፡ ሳልባት ፤ ከበባት ፥ ምሽግም ፡ ሥራባት ፥ አፈርም ፡ ደልድልባት ፥ ሰፈርም ፡ አቁምባት ፥ በዙሪያዋም ፡ የሚያፈርስ ፡ ግንድ ፡ ፫ አድርግባት ። የብረት ፡ ምጣድም ፡ ወስደህ ፡ በአንተና ፡ በከተማይቱ ፡ መካከል ፡ ለብረት ፡ ቅጥር ፡ አድርገው ፥ ፊትህንም ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ አቅና ፥ የተከበበችም ፡ ትሆናለች ፡ አንተም ፡ ትከብባታለህ ። ይህም ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ ምልክት ፡ ይሆናል ።

፬ አንተም ፡ በግራ ፡ ጐድንህ ፡ ተኛ ፡ የእስራኤልንም ፡ ቤት ፡ ኃጢአት ፡ አኑርበት ፤ በምትተኛበትም ፡ ቀን ፡ ቍጥር ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ትሸ ፭ ከማለህ ። እኔም ፡ የኃጢአታቸውን ፡ ዓመታት ፡ ለአንተ ፡ የቀን ፡ ቍጥር ፡ እንዲሆንልህ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ዘጠና ፡ ቀን ፡ ሰጥቼሃለሁ ፤ የእስራኤልንም ፡ ቤት ፡ ኃጢአት ፡ ትሸከማለህ ። ፮ እነዚህንም ፡ በፈጸምህ ፡ ጊዜ ፡ በቀኝ ፡ ጐድንህ ፡ ትተኛለህ ፥ የይሁዳንም ፡ ቤት ፡ ኃጢአት ፡ ትሸከማለህ ፤ አንድን ፡ ዓመት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ አድርጌ ፡ አርባ ፡ ፯ ቀን ፡ ሰጥቼሃለሁ ። ክንድህን ፡ ዕራቁቱን ፡ አድርገህ ፡ ፊትህን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ከበባ ፡ ታቀ ፰ ናለህ ፥ ትንቢትም ፡ ትናገርበታለህ ። እነሆም ፥ ገመድ ፡ አደርግብሃለሁ ፥ የምትከበብበትንም ፡ ወራት ፡ እስክትፈጽም ፡ ድረስ ፡ ከጐድን ፡ ጐድንህ ፡ አትገላበጥም ።

፱ አንተም ፡ ስንዴንና ፡ ገብስን ፡ ባቄላንና ፡ ምስርን ፡ ጤፍንና ፡ አጃን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ውሰድ ፥ በአንድ ፡ ዕቃም ፡ ውስጥ ፡ አድርገህ ፡ እንጀራ ፡ ጋግር ፤ በጐድንህ ፡ እንደ ፡ ተኛህበት ፡ ቀን ፡ ቍጥር ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ዘጠና ፡ ቀን ፡ ትበላዋለህ ። ፲ የምትበላውም ፡ በሚዛን ፡ በየቀኑ ፡ ሀያ ፡ ሀያ ፡ ፲፩ ሰቅል ፡ ይሁን ፥ በየጊዜው ፡ ትበላዋለህ ። ውኃውንም ፡ በልክ ፡ የኢን ፡ መስፈሪያ ፡ ከስድስት ፡ እጅ ፡ አንድን ፡ እጅ ፡ ትጠጣለህ ፥ በየጊዜው ፡ ትጠጣዋለህ ። ፲፪ እንደ ፡ ገብስ ፡ እንጐቻም ፡ አድርገህ ፡ ትበላዋለህ ፥ ከሰውም ፡ በሚወጣ ፡ ፋን ፲፫ ድያ ፡ በፊታቸው ፡ ትጋግረዋለህ ። እግዚአብሔርም ፦ እንዲሁ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እነርሱን ፡ በምበትንባቸው ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ርኵስ ፡ እንጀራቸውን ፡ ይበላሉ ፡ አለ ። ፲፬ እኔም ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ ወዮ ! እነሆ ፥ ሰውነቴ ፡ አልረከሰችም ፤ ከታናሽነቴ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ጥንብና ፡ አውሬ ፡ የሰበረው ፡ ከቶ ፡ አልበላሁም ፥ ርኵስም ፡ ሥጋ ፡ በአፌ ፡ ውስጥ ፡ አልገባም ፡ አልሁ ። ፲፭ እርሱም ፦ እነሆ ፥ በሰው ፡ ፋንድያ ፡ ፋንታ ፡ ኩበት ፡ ሰጥቼሃለሁ ፡ በእርሱም ፡ እንጀራህን ፡ ትጋግራለህ ፡ ፲፮ አለኝ ። ደግሞም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ የኢየሩሳሌምን ፡ እንጀራ ፡ በትር ፡ እሰብራለሁ ፥ እየፈሩም ፡ እንጀራን ፡ በሚዛን ፡ ይበላሉ ፥ እየደነገጡም ፡ ውኃን ፡ በልክ ፡ ይጠ ፲፯ ጣሉ ፤ ይህም ፡ እንጀራንና ፡ ውኃን ፡ እንዲያጡ ፥ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ እንዲደነቁ ፥ በኃጢአታቸውም ፡ እንዲሰለሱ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ አንተም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፡ የተሳለን ፡ ጐራዴ ፡ ውሰድ ፡ እንደ ፡ ጢም ፡ መላጫ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ትወስደዋለህ ፡ ራስህንና ፡ ጢምህንም ፡ ትላጭበታለህ ፤ ሚዛንንም ፡ ውሰድ ፡ ጠጕሩንም ፡ ትከፋፍላለህ ። ፪ የመከበብም ፡ ወራት ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ በከተማይቱ ፡ መካከል ፡ ሢሶውን ፡ በእሳት ፡ ታቃጥላለህ ፤ ሢሶውንም ፡ ወስደህ ፡ ዙሪያውን ፡ በጐራዴ ፡ ትመታለህ ፡ ሢሶውንም ፡ ወደ ፡ ነፋስ ፡ ትበትናለህ ፤ እኔም ፡ በኋላቸው ፡ ጐራዴ ፡ እመዝዛለሁ ። ፫ ከዚያም ፡ በጥቂቱ ፡ ውሰድ ፡ በመጐናጸፊያህም ፡ ጫፍ ፡ ቋጥራቸው ። ፬ ከእነርሱም ፡ ደግሞ ፡ ወስደህ ፡ በእሳት ፡ ውስጥ ፡ ትጥላለህ ፡ በእሳትም ፡ ታቃጥላቸዋለህ ፤ ከዚያም ፡ በእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እሳት ፡ ትወጣለች ።

፭ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ይህች ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ናት ፤ በአሕዛብም ፡ መካከል ፡ አድርጌአታለሁ ፡ አገሮችም ፡ በዙሪያዋ ፡ አሉ ። ፮ እርስዋም ፡ ከአሕዛብ ፡ ይልቅ ፡ ፍርዴን ፡ በኃጢአት ፡ ለወጠች ፡ በዙሪያዋም ፡ ካሉ ፡ አገሮች ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ትእዛዜን ፡ ተላለፈች ፤ ፍርዴን ፡ ጥለዋልና ፡ በትእዛዜም ፡ አልሄዱምና ። ፯ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ በዙሪያችሁ ፡ ካሉት ፡ አሕዛብ ፡ ሰበብ ፡ ሆናችኋልና ፡ በትእዛዜም ፡ አልሄዳችሁምና ፡ ፍርዴንም ፡ አልጠበቃችሁምና ፡ በዙሪያችሁም ፡ እንዳሉ ፡ እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ፍርድ ፡ እንኳ ፡ አላደረጋችሁምና ፡ ፰ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እነሆ ፡ እኔ ፡ ራሴ ፡ በአንቺ ፡ ላይ ፡ ነኝ ፡ አሕዛብም ፡ እያዩ ፡ ፍርድን ፡ በመካከልሽ ፡ አደርጋለሁ ። ፱ ስለ ፡ ርኵሰትሽም ፡ ሁሉ ፡ ያልሠራሁትን ፡ እርሱንም ፡ የሚመስል ፡ ደግሞ ፡ የማልሠራውን ፡ ነገር ፡ እሠራብሻለሁ ። ፲ ስለዚህ ፡ በመካከልሽ ፡ አባቶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ ይበላሉ ፡ ልጆችም ፡ አባቶቻቸውን ፡ ይበላሉ ፤ ፍርድንም ፡ አደርግብሻለሁ ፡ ከአንቺም ፡ የቀረውን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ነፋሳት ፡ ሁሉ ፡ እበትናለሁ ። ፲፩ ስለዚህ ፡ እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ በእድፍሽና ፡ በርኵሰትሽ ፡ መቅደሴን ፡ ስላረከስሽ ፡ ስለዚህ ፡ በእውነት ፡ እኔ ፡ አሳንስሻለሁ ፡ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ ዓይኔም ፡ አይራራም ፡ እኔም ፡ አላዝንም ። ፲፪ ከአንቺም ፡ ሢሶው ፡ በቸነፈር ፡ ይሞታል ፡ በመካከልሽም ፡ በራብ ፡ ያልቃል ፤ ሢሶውም ፡ በዙሪያሽ ፡ በሰይፍ ፡ ይወድቃል ፤ ሢሶውንም ፡ ወደ ፡ ነፋሳት ፡ ሁሉ ፡ እበትናለሁ ፡ በኋላቸውም ፡ ሰይፍ ፡ እመዝዛለሁ ።

፲፫ ቍጣዬም ፡ ይፈጸማል ፡ መዓቴንም ፡ እጨርሳለሁ ፡ እጽናናማለሁ ፡ መዓቴንም ፡ በፈጸምሁባቸው ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ በቅንዓቴ ፡ እንደ ፡ ተናገርሁ ፡ ያውቃሉ ። ፲፬ በዙሪያሽም ፡ ባሉ ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ በሚያልፉም ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ባድማና ፡ መሰደቢያ ፡ አደርግሻለሁ ። ፲፭ በቍጣና ፡ በመዓት ፡ በመዓትም ፡ ዘለፋ ፡ ፍርድን ፡ ባደረግሁብሽ ፡ ጊዜ ፡ በዙሪያሽ ፡ ላሉ ፡ አሕዛብ ፡ መሰደቢያና ፡ መተረቻ ፡ ተግሣጽና ፡ መደነቂያ ፡ ይሆናል ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ተናግሬአለሁ ። ፲፮ ለማጥፋትም ፡ የሆነውን ፡ አጠፋችሁም ፡ ዘንድ ፡ የምሰድደውን ፡ የራብ ፡ ፍላጻ ፡ በላያችሁ ፡ በሰደድሁ ፡ ጊዜ ፡ ራብን ፡ እጨምርባችኋለሁ ፡ የእንጀራችሁንም ፡ በትር ፡ እሰብራለሁ ። ፲፯ ራብንና ፡ ክፉዎችን ፡ አራዊት ፡ እሰድድባችኋለሁ ፡ ልጆቻችሁንም ፡ ያጠፋሉ ፤ ቸነፈርና ፡ ደምም ፡ በአንቺ ፡ ዘንድ ፡ ያልፋሉ ፤ ሰይፍንም ፡ አመጣብሻለሁ ። እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ተናግሬአለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦ ፪ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፡ ፊትህን ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ተራሮች ፡ አቅና ፡ ትንቢትም ፡ ተናገርባቸው ። ፫ እንዲህም ፡ በል ፦ የእስራኤል ፡ ተራሮች ፡ ሆይ ፡ የጌታን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስሙ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለተራሮችና ፡ ለኮረብቶች ፡ ለምንጮችና ፡ ለሸለቆች ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እኔ ፡ እነሆ ፡ እኔ ፡ ሰይፍን ፡ አመጣባችኋለሁ ፡ የኮረብታው ፡ መስገጃዎቻችሁንም ፡ አጠፋለሁ ። ፬ መሠዊያዎቻችሁም ፡ ይፈርሳሉ ፡ የፀሐይም ፡ ምስሎቻችሁ ፡ ይሰበራሉ ፤ ተወግተውም ፡ የሞቱትን ፡ ሰዎቻችሁን ፡ በጣዖቶቻችሁ ፡ ፊት ፡ እጥላለሁ ። ፭ የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ ሬሳዎች ፡ በጣዖቶቻቸው ፡ ፊት ፡ እኖራለሁ ፡ አጥንቶቻችሁንም ፡ በመሠዊያዎቻችሁ ፡ ዙሪያ ፡ እበትናለሁ ። ፮ በምትኖሩበትም ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ ከተሞቹ ፡ ይፈርሳሉ ፡ የኮረብታው ፡ መስገጃዎችም ፡ ሁሉ ፡ ውድማ ፡ ይሆናሉ ፡ መሠዊያዎቻችሁም ፡ ይፈርሳሉ ፡ ባድማም ፡ ይሆናሉ ፡ ጣዖቶቻችሁም ፡ ይሰበራሉ ፡ ያልቃሉም ፡ የፀሐይም ፡ ምስሎቻችሁ ፡ ይቈረጣሉ ፡ ሥራችሁም ፡ ይሻራል ። ፯ ተወግተውም ፡ የሞቱ ፡ በመካከላችሁ ፡ ይወድቃሉ ፡ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ።

፰ ነገር ፡ ግን ፡ በአገሮች ፡ በተበተናችሁ ፡ ጊዜ ፡ ከሰይፍ ፡ ያመለጡትን ፡ ቅሬታ ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ አስቀርላችኋለሁ ። ፱ ከእናንተም ፡ የዳኑት ፡ ከእኔ ፡ በራቀው ፡ በአመንዝራ ፡ ልባቸውና ፡ ጣዖቶቻቸውን ፡ በተከተሉ ፡ በአመንዝራ ፡ ዓይኖቻቸው ፡ የተሰበርሁትን ፡ እኔን ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ በተማረኩት ፡ አሕዛብ ፡ መካከል ፡ ሆነው ፡ ያስቡኛል ፤ በርኵሰታቸውም ፡ ሁሉ ፡ ስላደረጉት ፡ ክፋት ፡ ራሳቸውን ፡ ይጸየፋሉ ። ፲ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ፤ ይህን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደርግባቸው ፡ ዘንድ ፡ መናገሬ ፡ በከንቱ ፡ አይደለም ።

፲፩ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ በእጅህ ፡ አጨብጭብ ፡ በእግርህም ፡ አሸብሽብ ፡

እንዲህም ፡ በል ፡— በሰይፍና ፡ በራብ ፡ በቸነፈ
ርም ፡ ይወድቃሉና ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡ ቤት ፡
ስለ ፡ አስጸያፊ ፡ ሥራዎቻቸው ፡ ሁሉ ፡ ወዮ !
፲፪ ፤ በሩቅ ፡ ያለው ፡ በቸነፈር ፡ ይሞታል ፥ በቅር
ብም ፡ ያለው ፡ በሰይፍ ፡ ይወድቃል ፥ የቀረ
ውና ፡ የዳነውም ፡ በራብ ፡ ይሞታል ፤ እንዲሁ ፡
፲፫ ፤ መዓቴን ፡ እፈጽምባቸዋለሁ ። ተወግተውም ፡
የሞቱ ፡ ሰዎቻቸው ፡ በጣዖቶቻቸው ፡ መካከልና ፡
በመሠዊያዎቻቸው ፡ ዙሪያ ፥ ለጣዖቶቻቸው ፡
ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ በቀረቡበት ፡ ስፍራ ፥ ከፍ ፡
ባለው ፡ ኮረብታ ፡ ሁሉ ፡ በተራሮችም ፡ ራስ ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፥ ከለመለመውም ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡
በታች ፡ ቅጠሉም ፡ ከበዛ ፡ ከአድባር ፡ ዛፍ ፡
ሁሉ ፡ በታች ፡ በሆኑ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ እግዚአብ
፲፬ ፤ ሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ። እጄንም ፡
እዘረጋባቸዋለሁ ፥ በሚኖሩበትም ፡ ስፍራ ፡
ሁሉ ፡ ምድሪቱን ፡ ከዴብላታ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
ይልቅ ፡ ውድማና ፡ በረሀ ፡ አደርጋታለሁ ፤ እኔም ፡
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፪ ፤ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— አንተ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡
ሆይ ፥ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእስራኤል ፡ ምድር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— ፍጻሜ ፥ በምድሪቱ ፡ በአ
፫ ፤ ራቱ ፡ ማዕዘን ፡ ላይ ፡ ፍጻሜ ፡ ደርሶአል ። አሁን ፡
ፍጻሜ ፡ በአንቺ ፡ ላይ ፡ ነው ፥ ቍጣዬንም ፡
እሰድድብሻለሁ ፥ እንደ ፡ መንገድሽም ፡ መጠን ፡
እፈርድብሻለሁ ፥ ርኵሰትሽንም ፡ ሁሉ ፡
፬ ፤ አመጣብሻለሁ ። ዓይኔም ፡ አይራራልሽም ፡
እኔም ፡ አላዝንም ፤ መንገድሽንም ፡ አመጣብሻ
ለሁ ፡ ርኵሰትሽም ፡ በመካከልሽ ፡ ይሆናል ፥
እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታው
ቃላችሁ ።
፭ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ክፉ ፡ ነገር ፥ አንድ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፥ እነሆ ፥ ይመ
፮ ፤ ጣል ። ፍጻሜ ፡ መጥቶአል ፥ ፍጻሜ ፡ መጥቶ
፯ ፤ አል ፥ ነቅቶብሻል ፤ እነሆ ፥ ደርሶአል ። በም
ድር ፡ የምትቀመጥ ፡ ሆይ ፥ ተራህ ፡ ደርሶአል ፥
ጊዜ ፡ መጥቶአል ፥ ቀን ፡ ቀርቦአል ፤ የሽብር ፡
ቀን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ ያለ ፡ እልልታ ፡
፰ ፤ አይደለም ። አሁን ፡ በቅርብ ፡ መዓቴን ፡ አፈስ
ስብሻለሁ ፥ ቍጣዬንም ፡ እፈጽምብሻለሁ ፥
እንደ ፡ መንገድሽም ፡ መጠን ፡ እፈርድብሻለሁ ፥
፱ ፤ ርኵሰትሽንም ፡ ሁሉ ፡ አመጣብሻለሁ ። ዓይ
ኔም ፡ አይራራም ፡ እኔም ፡ አላዝንም ፤ እንደ ፡
መንገድሽም ፡ መጠን ፡ አመጣብሻለሁ ፥ ርኵሰ
ትሽም ፡ በመካከልሽ ፡ ይሆናል ፥ እኔም ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ የምቀሥፍ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታው
ቃላችሁ ።
፲ ፤ እነሆ ፡ ቀኑ ፥ እነሆ ፥ መጥቶአል ፤ ተራህ ፡
ወጥቶአል ፤ በትር ፡ አብቦአል ፥ ትዕቢትም ፡
፲፩ ፤ አቈብቍሎአል ። ግፍ ፡ ወደ ፡ ክፋት ፡ በትር ፡
ተነሥቶአል ፤ ከእነርሱና ፡ ከብዛታቸው ፡ ከሀብ
ታቸውም ፡ ምንም ፡ አይቀርም ፥ የሚያለቅስላ
፲፪ ፤ ቸውም ፡ የለም ። ጊዜው ፡ መጥቶአል ፥ ቀኑ ፡
ቀርቦአል ፤ መዓት ፡ በብዙዎች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡
ነውና ፡ የሚገዛ ፡ ደስ ፡ አይበለው ፡ የሚሸጥም ፡
፲፫ ፤ አያልቅስ ። የሚሸጥ ፡ ወደ ፡ ሸጠው ፡ ነገር ፡
አይመለስም ፥ ሰውም ፡ በነፍሱ ፡ ኃጢአት ፡
አይጸናም ።
፲፬ ፤ መለከቱን ፡ ነፍተዋል ፡ ሁሉንም ፡ አዘጋጅተ
ዋል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ መዓቴ ፡ በብዙዎች ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ ነውና ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ የሚሄድ ፡ የለም ።
፲፭ ፤ ሰይፍ ፡ በውጭ ፡ ቸነፈርና ፡ ራብ ፡ በውስጥ ፡ አለ ፤
በሜዳ ፡ ያለው ፡ በሰይፍ ፡ ይሞታል ፥ በከተ
ማም ፡ ያለውን ፡ ቸነፈርና ፡ ራብ ፡ ይፈጁታል ።
፲፮ ፤ ከእነርሱም ፡ የሚሸሹ ፡ ይድናሉ ፡ በተራራም ፡
ላይ ፡ ይሆናሉ ፤ እኔም ፡ በኃጢአታቸው ፡ ሁሉን ፡
፲፯ ፤ እገድላለሁ ። እጅ ፡ ሁሉ ፡ ትደክማለች ፡ ጕልበ
፲፰ ፤ ትም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ ትቀልጣለች ። ማቅም ፡
ይለብሳሉ ፡ ድንጋጤም ፡ ይሸፍናቸዋል ፤ በፊ
ትም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እፍረት ፡ ይሆናል ፥ ራሳቸ
፲፱ ፤ ውንም ፡ ሁሉ ፡ ይነጩታል ። ብራቸውን ፡ በጎ
ዳናዎቹ ፡ ላይ ፡ ይጥላሉ ፡ ወርቃቸውም ፡ እንደ ፡
ጕድፍ ፡ ይሆናል ፤ በእግዚአብሔር ፡ መዓት ፡
ቀን ፡ ብራቸውና ፡ ወርቃቸው ፡ ያድናቸው ፡
ዘንድ ፡ አይችልም ። እርሱ ፡ የኃጢአታቸው ፡
ዕንቅፋት ፡ ሆኖአልና ፡ ሰውነታቸውን ፡ አያጠግ
፳ ፤ ቡም ፡ ሆዳቸውንም ፡ አይሞሉም ። የክብሩንም ፡
ጌጥ ፡ ወደ ፡ ትዕቢት ፡ ለወጡ ፥ የርኵስነታቸ
ውንም ፡ ምስሎች ፡ አደረጉበት ፤ ስለዚህ ፡ እኔ ፡
በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ርኩስ ፡ አድርጌአታለሁ ።
፳፩ ፤ በባዕድም ፡ እጅ ፡ ለንጥቂያ ፥ በምድር ፡ ኃጢአ
ተኞችም ፡ እጅ ፡ ለብዝበዛ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣታ
፳፪ ፤ ለሁ ፤ እነርሱም ፡ ያረክሱአታል ። ፊቴን ፡ ከእ
ነርሱ ፡ ዘንድ ፡ እመልሳለሁ ፥ ምሥጢሬንም ፡
ያረክሳሉ ፤ ወንበዴዎችም ፡ ይገቡባታል ፡ ያረ
ክሱአትማል ።
፳፫ ፤ ምድር ፡ ደም ፡ ባመጣው ፡ በደል ፥ ከተማም ፡
፳፬ ፤ በግፍ ፡ ተሞልታለችና ፡ ሰንሰለት ፡ ሥራ ። ከአ
ሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ከሁሉ ፡ የሚከፉትን ፡ አመጣ
ለሁ ፡ ቤቶቻቸውንም ፡ ይወርሳሉ ፤ የኃያላን
ንም ፡ ትዕቢት ፡ አጠፋለሁ ፥ መቅደሶቻቸውም ፡
፳፭ ፤ ይረከሳሉ ። ጥፋት ፡ መጥቶአል ፤ ሰላምም ፡
፳፮ ፤ ይሻሉ ፡ እርሱም ፡ አይገኝም ። ድንጋጤ ፡ በድ
ንጋጤ ፡ ላይ ፡ ይመጣል ፥ ወሬም ፡ ወሬውን ፡
ይከተላል ፥ ከነቢዩም ፡ ዘንድ ፡ ራእይን ፡ ይሻሉ ፤
ከካህኑም ፡ ዘንድ ፡ ትምህርት ፥ ከሽማግሌዎ
፳፯ ፤ ችም ፡ ዘንድ ፡ ምክር ፡ ይጠፋል ። ንጉሡም ፡ ያለ
ቅሳል ፥ አለቃም ፡ ውርደትን ፡ ይለብሳል ፥ የም
ድርም ፡ ሕዝብ ፡ እጅ ፡ ትንቀጠቀጣለች ፤ እንደ ፡
መንገዳቸውም ፡ መጠን ፡ አደርግባቸዋለሁ ፥
በፍርዳቸውም ፡ መጠን ፡ እፈርድባቸዋለሁ ፤
እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያው
ቃሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ በስድስተኛውም ፡ ዓመት ፡ በስድስተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአምስተኛው ፡ ቀን ፡ በቤቴ ፡ ተቀምጬ ፡ ሳለሁ ፡ የይሁዳም ፡ ሽማግሌዎች ፡ በፊቴ ፡ ተቀምጠው ፡ ሳሉ ፥ በዚያ ፡ የጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ በላዬ ፡ ወደቀች ። ፪ እኔም ፡ አየሁ ፥ እነሆም ፥ እንደ ፡ እሳት ፡ የሚመስል ፡ አምሳያ ፡ ነበረ ፤ ከወገቡም ፡ ምሳሌ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ እሳት ፡ ነበረ ፥ ከወገቡም ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ፀዳል ፡ ምሳሌ ፥ እንደሚብለጨለጭም ፡ የወርቅ ፡ ምሳሌ ፡ ነበረ ። ፫ እጅ ፡ መሳይንም ፡ ዘረጋ ፡ በራስ ፡ ጠጕሬም ፡ ያዘኝ ፤ መንፈስም ፡ በምድርና ፡ በሰማይ ፡ መካከል ፡ አነሣኝ ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ራእይ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ወደሚመለከተው ፡ ወደ ፡ ውስጠኛው ፡ አደባባይ ፡ በር ፡ መግቢያ ፡ አመጣኝ ፤ በዚያም ፡ ቅንዓት ፡ የሚያነሣሣ ፡ የቅንዓት ፡ ጣዖት ፡ ተተክሎ ፡ ነበር ። ፬ እነሆም ፥ በቈላው ፡ እንዳየሁት ፡ ራእይ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ክብር ፡ በዚያ ፡ ነበረ ።

፭ እርሱም ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ዓይንህን ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ መንገድ ፡ አንሣ ፡ አለኝ ። ዓይኔንም ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ መንገድ ፡ አነሣሁ ፤ እነሆም ፥ በመሠዊያው ፡ በር ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ በመግቢያው ፡ ይህ ፡ የቅንዓት ፡ ጣዖት ፡ ነበረ ። ፮ እርሱም ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ የሚያደርጉትን ፥ ከመቅደሴ ፡ ያርቁኝ ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ በዚህ ፡ የሚያደርጉትን ፡ ታላቁን ፡ ርኵሰት ፡ ታያለህን ? ደግሞም ፡ ተመልሰህ ፡ ከዚህ ፡ የበለጠ ፡ ታላቅ ፡ ርኵሰት ፡ ታያለህ ፡ አለኝ ።

፯ ወደ ፡ አደባባዩም ፡ መግቢያ ፡ አመጣኝ ፤ በየሁም ፡ ጊዜ ፥ እነሆ ፥ በግንቡ ፡ ውስጥ ፡ ቀዳዳ ፡ ነበረ ። ፰ እርሱም ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ግንቡን ፡ ንደለው ፡ አለኝ ፤ ግንቡንም ፡ በነደልሁት ፡ ጊዜ ፡ መዝጊያ ፡ አገኘሁ ። ፱ እርሱም ፡— ግባ ፥ በዚህም ፡ የሚያደርጉትን ፡ ክፉውን ፡ ርኵሰት ፡ እይ ፡ አለኝ ። ፲ እኔም ፡ ገባሁና ፡ እነሆ ፥ በግንቡ ፡ ዙሪያ ፡ ላይ ፡ የተንቀሳቃሾችና ፡ የርኩሳን ፡ አራዊት ፡ ምሳሌ ፡ የእስራኤልንም ፡ ቤት ፡ ጣዖታት ፡ ሁሉ ፡ ተስለው ፡ አየሁ ። ፲፩ በፊታቸውም ፡ ከእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሰባ ፡ ሰዎች ፡ ቆመው ፡ ነበር ፥ በመካከላቸውም ፡ የሳፋን ፡ ልጅ ፡ ያእዛንያ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፥ ሰውም ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ በእጁ ፡ ጥናውን ፡ ይዞ ፡ ነበር ፥ የዕጣኑም ፡ ጢስ ፡ ሽቱ ፡ ይወጣ ፡ ነበር ። ፲፪ እርሱም ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሽማግሌዎች ፡ በጨለማ ፡ እያንዳንዱ ፡ በስዕሉ ፡ ቤት ፡ የሚያደርጉትን ፡ አይተሃልን ? እነርሱ ፡— እግዚአብሔር ፡ አያየንም ፤ እግዚአብሔር ፡ ምድሪቱን ፡ ትቶአታል ፡ ይላሉና ፡ አለኝ ። ፲፫ እርሱም ፡— ደግሞ ፡ ተመልሰህ ፡ ከዚህ ፡ የበለጠውን ፡ የሚያደርጉትን ፡ ታላቅ ፡ ርኵሰት ፡ ታያለህ ፡ አለኝ ።

፲፬ ወደ ፡ ሰሜንም ፡ ወደሚመለከተው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በር ፡ መግቢያ ፡ አመጣኝ ፤ እነሆም ፥ ሴቶች ፡ ለተሙዝ ፡ እያለቀሱ ፡ በዚያ ፡ ተቀምጠው ፡ ነበር ። ፲፭ እርሱም ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ አይተሃልን ? ደግሞ ፡ ተመልሰህ ፡ ከዚህ ፡ የበለጠ ፡ ርኵሰት ፡ ታያለህ ፡ አለኝ ።

፲፮ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ውስጠኛው ፡ አደባባይ ፡ አመጣኝ ፥ እነሆም ፥ በእግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ መግቢያ ፡ ፊት ፡ በወለሉና ፡ በመሠዊያው ፡ መካከል ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ የሚያህሉ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፡ ጀርባቸውም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ ፊታቸውም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ነበረ ፤ እነርሱም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ለፀሐይ ፡ ይሰግዱ ፡ ነበር ። ፲፯ እርሱም ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ አይተሃልን ? በዚህ ፡ የሚያደርጉትን ፡ ይህን ፡ ርኵሰት ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ለይሁዳ ፡ ቤት ፡ ጥቂት ፡ ነገር ፡ ነውን ? ምድሪቱን ፡ በግፍ ፡ ሞልተዋታል ፡ ያስቈጡኝም ፡ ዘንድ ፡ ተመልሰዋል ፤ እነሆም ፥ ቅርንጫፉን ፡ ወደ ፡ አፍንጫው ፡ አቅርበዋል ። ፲፰ ስለዚህ ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ በመዓት ፡ እሠራለሁ ፤ ዓይኔ ፡ አይራራም ፡ እኔም ፡ አላዝንም ፤ ወደ ፡ ጆሮዬም ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ቢጮኹ ፡ አልሰማቸውም ፡ አለኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ እርሱም ፡— እያንዳንዳቸው ፡ የሚያጠፉ ፡ መሣሪያን ፡ በእጃቸው ፡ ይዘው ፡ ከተማይቱን ፡ የሚቀሥፉ ፡ ይቅረቡ ፡ ብሎ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ በጆሮዬ ፡ ጮኸ ። ፪ እነሆም ፥ እያንዳንዳቸው ፡ አጥፊውን ፡ መሣሪያ ፡ በእጃቸው ፡ ይዘው ፡ ስድስት ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ከሚመለከተው ፡ ከላይኛው ፡ በር ፡ መንገድ ፡ መጡ ፤ በመካከላቸውም ፡ የበፍታ ፡ ልብስ ፡ የለበሰ ፡ የጸሐፊም ፡ ቀለም ፡ ቀንድ ፡ በወገቡ ፡ የያዘ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበረ ። እነርሱም ፡ ገብተው ፡ በናሱ ፡ መሠዊያ ፡ አጠገብ ፡ ቆሙ ።

፫ የእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ ክብር ፡ በበላዩ ፡ ከነበረበት ፡ ኪሩብ ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ መድረክ ፡ ሄዶ ፡ ነበር ፤ በፍታም ፡ የለበሰውን ፡ የጸሐፊውንም ፡ ቀለም ፡ ቀንድ ፡ በወገቡ ፡ የያዘውን ፡ ሰው ፡ ጠራ ። ፬ እግዚአብሔርም ፡— በከተማይቱ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ መካከል ፡ እለፍ ፥ በመካከልዋም ፡ ስለ ፡ ተሠራው ፡ ርኵሰት ፡ ሁሉ ፡ በሚያለቅሱና ፡ በሚተክዙ ፡ ሰዎች ፡ ግምባር ፡ ላይ ፡ ምልክት ፡ ጻፍ ፡ አለው ። ፭ እኔም ፡ እየሰማሁ ፡ ለሌሎቹ ፡— እርሱን ፡ ተከትላችሁ ፡ በከተማይቱ ፡ መካከል ፡ እለፉ ፡ ግደሉም ፤ ዓይናችሁ ፡ አይራራ ፡ አትዘኑም ፤ ፮ ሽማግሌውንና ፡ ጕበዙን ፡ ቈንጆይቱንም ፡ ሕፃናቶቹንና ፡ ሴቶቹን ፡ ፈጽማችሁ ፡ ግደሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ምልክቱ ፡ ወዳለበት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ አትቅረቡ ፤ በመቅደሴም ፡ ጀምሩ ፡ አላቸው ። በቤቱም ፡ አንጻር ፡ ባሉ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ጀመሩ ። ፯ እርሱም ፡— ቤቱን ፡

አርከሱ ÷ በተገደሉትም ፡ ሰዎች ፡ አደባባዮ
ችን ፡ ሙሉ ፤ ውጡ ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡ ወጥ
፰ ተው ፡ በከተማይቱ ፡ ገደሉ ። ሲገድሉም ፡ እኔ ፡
ብቻዬን ፡ ቀርቼ ፡ ሳለሁ ፡ በግምባሬ ፡ ተደ
ፍቼ ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ÷ ወዮ !
መዓትህን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ ስታፈስስ ፡ የእ
ስራኤልን ፡ ቅሬታ ፡ ሁሉ ፡ ታጠፋለህን ? ብዬ ፡
ጮኽሁ ።

፱ እርሱም ፡— የእስራኤልና ፡ የይሁዳ ፡ ቤት ፡
ኃጢአት ፡ እጅግ ፡ በዝቶአል ፡ ምድሪቱም ፡
ደም ÷ ከተማይቱም ፡ ዓመፅን ፡ ተሞልታለች ፤
እነርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡ ምድሪቱን ፡ ትቶ
አታል ፡ እግዚአብሔርም ፡ አያይም ፡ ብለዋል ።
፲ እኔም ፡ ደግሞ ፡ በዓይኔ ፡ አልራራም ፡ አላዝን
ምም ÷ መንገዳቸውንም ፡ በራሳቸው ፡ ላይ ፡
፲፩ እመልሳለሁ ፡ አለኝ ። እነሆም ÷ በፍታ ፡ የለበ
ሰው ፡ የቀለም ፡ ቀንድም ፡ በወገቡ ፡ የያዘው ፡
ሰው ፡— ያዘዝኸኝን ፡ አድርጌአለሁ ፡ ብሎ ፡
በቃሉ ፡ መለሰ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ እኔም ፡ አየሁ ፥ እነሆም ÷ በኪሩቤል ፡ ራስ ፡
ላይ ፡ ባለው ፡ ጠፈር ፡ በላያቸው ፡ እንደ ፡ ሰን
ፔር ፡ ድንጋይ ፡ ያለ ፡ እንደ ፡ ዙፋን ፡ የሚመ
፪ ስል ፡ መልክ ፡ ተገለጠ ። በፍታም ፡ የለበሰውን ፡
ሰው ፡— በመንኰራኵሮች ፡ መካከል ፡ ከኪሩብ ፡
በታች ፡ ግባ ÷ ከኪሩቤልም ፡ መካከል ፡ ካለው ፡
እሳት ፡ ፍም ፡ እጆችህን ፡ ሙላ ፡ በከተማይቱም ፡
ላይ ፡ በትናት ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ። እኔም ፡ እያ
፫ የሁ ፡ ገባ ። ሰውዬውም ፡ ሲገባ ፡ ኪሩቤል ፡
በቤቱ ፡ ቀኝ ፡ በኩል ፡ ቆመው ፡ ነበር ÷ ደመና
፬ ውም ፡ ውስጠኛውን ፡ አደባባይ ፡ሞላ ። የእ
ግዚአብሔር ፡ ክብርም ፡ ከኪሩቤል ፡ ወጥቶ ፡
በቤቱ ፡ መድረክ ፡ ላይ ፡ ቆመ ፤ ቤቱም ፡ በደመ
ናው ፡ ተሞላ ÷ አደባባዩም ፡ በእግዚአብሔር ፡
፭ ክብር ፡ ፀዳል ፡ ተሞላ ። ሁሉንም ፡ የሚችል ፡
አምላክ ፡ እንደሚናገረው ፡ ያለ ፡ ድምፅ ፡ እን
ዲሁ ፡ የኪሩቤል ፡ ክንፎች ፡ ድምፅ ፡ እስከ ፡
፮ ውጭው ፡ አደባባይ ፡ ድረስ ፡ ተሰማ ። በፍታም ፡
የለበሰውን ፡ ሰው ፡— ከመንኰራኵሮች ፡ ከኪ
ሩቤል ፡ መካከል ፡ እሳት ፡ ውሰድ ፡ ብሎ ፡ በዘ
ዘው ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ ገብቶ ፡ በአንድ ፡ መንኰራ
፯ ኵር ፡ አጠገብ ፡ ቆመ ። ኪሩብም ፡ ከኪሩቤል ፡
መካከል ፡ እጁን ፡ በኪሩቤል ፡ መካከል ፡ ወዳ
ለው ፡ እሳት ፡ ዘርግቶ ፡ ከዚያ ፡ ወሰደ ÷ በፍ
ታም ፡ በለበሰው ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ አኖረው ፤ እር
፰ ሱም ፡ ይዞ ፡ ወጣ ። በኪሩቤልም ፡ ከክንፎቻ
ቸው ፡ በታች ፡ የሰው ፡ እጅን ፡ መሳይ ፡ ታየ ።
፱ እኔም ፡ አየሁ ፥ እነሆም ÷ በኪሩቤል ፡ አጠ
ገብ ፡ አራት ፡ መንኰራኵሮች ፡ ነበሩ ፤ አንዱ ፡
መንኰራኵር ፡ በአንዱ ፡ ኪሩብ ÷ አንዱ ፡ መን
ኰራኵር ፡ በአንዱ ፡ ኪሩብ ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ።
የመንኰራኵሮቹም ፡ መልክ ፡ እንደ ፡ ቢረሌ ፡
፲ ድንጋይ ፡ ነበረ ። የአራቱም ፡ መልክ ፡ አንድ ፡
ይመስል ፡ ነበር ፥ መልካቸውም ፡ በመንኰራ
ኵር ፡ ውስጥ ፡ እንዳለ ፡ መንኰራኵር ፡ ነበረ ።
፲፩ ሲሄዱም ፡ በአራቱ ፡ ጐድናቸው ፡ ይሄዱ ፡ ነበር ፥
ሲሄዱም ፡ አይገላመጡም ፡ ነበር ÷ ራሱ ፡ ወደ
ምታመለክትበት ፡ ስፍራ ፡ ወደዚያ ፡ ይከተሉ ፡
፲፪ ነበር ፤ ሲሄዱም ፡ አይገላመጡም ፡ ነበር ። ገላቸ
ውም ፡ ሁሉ ፡ ጀርባቸውም ፡ እጃቸውም ፡ ክን
ፉቻውም ፡ መንኰራኵሮቹም ÷ ለአራቱ ፡ የነ
በሩ ፡ መንኰራኵሮች ÷ በዙሪያቸው ፡ ዓይኖች ፡
፲፫ ተሞልተው ፡ ነበር ። መንኰራኵሮችም ፡ እኔ ፡
፲፬ እየሰማሁ ፡ ጌልጌል ፡ ተብለው ፡ ተጠሩ ። ለእያ
ንዳንዱም ፡ አራት ፡ አራት ፡ ፊት ፡ ነበሩት ፤ አን
ደኛው ፡ ፊት ፡ የኪሩብ ፡ ፊት ÷ ሁለተኛውም ፡
የሰው ፡ ፊት ÷ ሦስተኛው ፡ የአንበሳ ፡ ፊት ÷
አራተኛውም ፡ የንስር ፡ ፊት ፡ ነበረ ።
፲፭ ኪሩቤልም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አሉ ፤ ይህ ፡ በኮበር ፡
፲፮ ወንዝ ፡ ያየሁት ፡ እንስሳ ፡ ነው ። ኪሩቤልም ፡
ሲሄዱ ፡ መንኰራኵሮቹ ፡ በአጠገባቸው ፡ ይሄዱ ፡
ነበር ፤ ኪሩቤልም ፡ ከምድር ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይሉ ፡
ዘንድ ፡ ክንፎቻቸውን ፡ ሲዘረጉ ፡ መንኰራኵ
ሮች ፡ ደግሞ ፡ ከአጠገባቸው ፡ ፈቀቅ ፡ አይሉም ፡
፲፯ ነበር ። ሕይወት ፡ ያላቸው ፡ የእንስሶች ፡ መን
ፈስ ፡ በመንኰራኵሮች ፡ ውስጥ ፡ ነበረና ፡ እነ
ዚህ ፡ ሲቆሙ ፡ እነዚያ ፡ ይቆሙ ፡ ነበር ÷ እነዚ
ህም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ሲሉ ፡ እነዚያ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡
ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይሉ ፡ ነበር ።
፲፰ የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ ከቤቱ ፡ መድረክ ፡
፲፱ ላይ ፡ ወጥቶ ፡ በኪሩቤል ፡ ላይ ፡ ቆመ ። ኪሩቤ
ልም ፡ ክንፎቻቸውን ፡ ዘረጉ ፡ እኔም ፡ እያየሁ ፡
ከምድር ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አሉ ፤ በወጡም ፡ ጊዜ ፡
መንኰራኵሮች ፡ በአጠገባቸው ፡ ነበሩ ፤ በእግ
ዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ በምሥራቁ ፡ በር ፡ መግ
ቢያ ፡ ቆሙ ÷ የእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ ክብር ፡
በላያቸው ፡ ላይ ፡ ነበረ ።
፳ ይህ ፡ በኮበር ፡ ወንዝ ፡ ከእስራኤል ፡ አምላክ ፡
በታች ፡ ያየሁት ፡ እንስሳ ፡ ነው ÷ ኪሩቤልም ፡
፳፩ እንደ ፡ ነበሩ ፡ አስተዋልሁ ። ለእያንዳንዱ ፡
አራት ፡ አራት ፡ ፊት ÷ ለእያንዳንዱም ፡ አራት ፡
አራት ፡ ክንፍ ፡ ነበሩት ÷ የሰውም ፡ እጅ ፡ አም
፳፪ ሳያ ፡ ከክንፎቻቸው ፡ በታች ፡ ነበረ ። ፊቶቻቸ
ውም ፡ በኮበር ፡ ወንዝ ፡ ያየኋቸውን ፡ ፊቶች ፡
ይመስሉ ፡ ነበር ፤ እነርሱና ፡ መልካቸውም ፡ እን
ዲሁ ፡ ነበረ ፤ እያንዳንዱም ፡ አቅንቶ ፡ ወደ ፡
ፊት ፡ ይሄድ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ መንፈስም ፡ አነሣኝ ፤ ወደ ፡ ፀሐይ ፡ መውጫ ፡
ወደሚመለከት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤትም ፡
ወደ ፡ ምሥራቁ ፡ በር ፡ አመጣኝ ። እነሆም ÷
በበሩ ፡ መግቢያ ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤
በመካከላቸውም ፡ የሕዝቡን ፡ አለቆች ፡ የዓዙ
ርን ፡ ልጅ ፡ ያእዛንያንና ፡ የበናያስ ፡ ልጅ ፡ ፈላ
፪ ጥያን ፡ አየሁ ። እርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡—
የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ እነዚህ ፡ ክፋትን ፡ የሚያ

ስቡ ፡ በዚህችም ፡ ከተማ ፡ ክፉን ፡ ምክር ፡ የሚ
፫ መክሩ ፡ ሰዎች ፡ ናቸው ። እነርሱም ፡— በውኑ ፡
ቤቶችን ፡ የምንሠራበት ፡ ዘመን ፡ የቀረበ ፡ አይ
ደለምን ? ይህች ፡ ከተማ ፡ ድስት ፡ እኛም ፡
፬ ሥጋ ፡ ነን ፡ ብለዋል ። ስለዚህ ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡
ሆይ ፥ ትንቢት ፡ ተናገርባቸው ፤ ትንቢት ፡
ተናገር ።

፭ የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ ወደቀ ብኝ ፡ እን
ዲህም ፡ አለኝ ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡ ብለህ ፡ ተናገር ፡— የእስራኤል ፡ ቤት ፡
ሆይ ፥ ይህን ፡ ነገር ፡ ተናግራችኋል ፥ እኔም ፡
፮ የልባችሁን ፡ አሳብ ፡ አውቃለሁ ። በዚህች ፡
ከተማ ፡ ውስጥ ፡ ግዳዮቻችሁን ፡ አብዝታችኋል ፡
፯ በጎዳናዎችዋም ፡ ግዳዮችን ፡ ሞልታችኋል ። ስለ
ዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
በመካከልዋ ፡ ያኖራችኋቸው ፡ ግዳዮቻችሁ ፡
እነርሱ ፡ ሥጋው ፡ ናቸው ፥ ይህችም ፡ ከተማ ፡
ድስቱ ፡ ናት ፤ እናንተን ፡ ግን ፡ ከመካከልዋ ፡
፰ አወጣችኋለሁ ። ሰይፍን ፡ ፈርታችኋል ፡ እኔም ፡
ሰይፍን ፡ አመጣባችኋለሁ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግ
፱ ዚአብሔር ። ከመካከልዋም ፡ አወጣችኋለሁ ፥
በእንግዶችም ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣችኋለሁ ፥
፲ በላያችሁም ፡ ፍርድ ፡ አደርጋለሁ ። በሰይፍ ፡
ትወድቃላችሁ ፡ በእስራኤልም ፡ ድንበር ፡ እፈ
ርድባችኋለሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡
፲፩ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ። ይህች ፡ ከተማ ፡ ድስት ፡
አትሆንላችሁም ፡ እናንተም ፡ በመካከልዋ ፡ ሥጋ ፡
አትሆኑም ፥ እኔም ፡ በእስራኤል ፡ ድንበር ፡ እፈ
ርድባችኋለሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡
፲፪ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ። በትእዛዜ ፡ አልሄዳች
ሁምና ፥ ፍርዴንም ፡ አላደረጋችሁምና ፤ በዙ
ሪያችሁም ፡ እንደሚኖሩት ፡ እንደ ፡ አሕዛብ ፡
ሕግ ፡ አድርጋችኋል ።

፲፫ ትንቢትም ፡ በተናገርሁ ፡ ጊዜ ፡ የበናያስ ፡
ልጅ ፡ ፈላጥያ ፡ ሞተ ፤ እኔም ፡ በግምባሬ ፡ ተደ
ፍቼ ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ ወዮ !
በውኑ ፡ የእስራኤልን ፡ ቅሬታ ፡ ፈጽመህ ፡ ታጠ
ፋለህን ? ብዬ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ጮኽሁ ።

፲፬ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፲፭ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ በኢየሩ
ሳሌም ፡ የሚኖሩ ፡— ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
ራቁ ፤ ይህች ፡ ምድር ፡ ርስት ፡ ሆና ፥ ለእኛ ፡ ተሰ
ጥታለች ፡ የሚሉአቸው ፡ ወንድሞችህና ፡ ዘመ
ዶችህ ፡ የወገኖችህም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ የእስራ
፲፮ ኤልም ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ናቸው ። ስለዚህ ፡— ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እኔ ፡ ወደ ፡
አሕዛብ ፡ አርቄአቸዋለሁ ፥ ወደ ፡ አገሮችም ፡
በትኜቸዋለሁ ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፥ በመጡባቸው ፡
አገሮች ፡ በእነዚያ ፡ ትንሽ ፡ መቅደስ ፡ እሆናቸ
፲፯ ዋለሁ ፡ በል ። ስለዚህም ፡ በል ፡— ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ከአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ አከማ
ቻችኋለሁ ፡ ከተበተናችሁባቸውም ፡ አገሮች ፡
እሰበስባችኋለሁ ፥ የእስራኤልንም ፡ ምድር ፡
፲፰ እሰጣችኋለሁ ። ወደዚያም ፡ ይመጣሉ ፥ ጸያፉ
ንና ፡ ርኩሱንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ከእርስዋ ፡ ያወ
፲፱ ጣሉ ። በትእዛዜም ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ፍርዴንም ፡ ፳
ይጠብቁና ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አንድ ፡ ልብ ፡ እሰ
ጣቸዋለሁ ፥ በውስጣቸውም ፡ አዲስ ፡ መንፈስ ፡
እሰጣለሁ ፥ ከሥጋቸውም ፡ ውስጥ ፡ የድንጋዩን ፡
ልብ ፡ አወጣለሁ ፡ የሥጋንም ፡ ልብ ፡ እሰጣቸዋ
ለሁ ፤ እነርሱም ፡ ሕዝብ ፡ ይሆኑኛል ፥ እኔም ፡
፳፩ አምላክ ፡ እሆናቸዋለሁ ። ልባቸውም ፡ ጸያፍ
ንና ፡ ርኩስን ፡ ነገር ፡ በሚከተል ፡ በእነርሱ ፡
ራስ ፡ ላይ ፡ መንገዳቸውን ፡ እመልሳለሁ ፥ ይላል ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፳፪ ኪሩቤልም ፡ ክንፎቻቸውን ፡ ዘረጉ ፥ መን
ኰራኵሮችም ፡ በአጠገባቸው ፡ ነበሩ ፤ የእስራ
ኤልም ፡ አምላክ ፡ ክብር ፡ በላያቸው ፡ ላይ ፡ ነበረ ።
፳፫ የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ ከከተማይቱ ፡ ውስጥ ፡
ተነሥቶ ፡ በከተማይቱ ፡ ምሥራቅ ፡ በኩል ፡
፳፬ ባለው ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ቆመ ። መንፈስም ፡ አነ
ሣኝ ፥ በእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ በራእይ ፡
ወደ ፡ ከላውዴዎን ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ ምርኮኞቹ ፡
አመጣኝ ። ያየሁትም ፡ ራእይ ፡ ከእኔ ፡ ወጥቶ ፡
፳፭ ተለየ ። እግዚአብሔርም ፡ ያሳየኝን ፡ ነገር ፡
ሁሉ ፡ ለምርኮኞች ፡ ተናገርሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡
፪ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ በዓመፀኛ ፡
ቤት ፡ መካከል ፡ ተቀምጠሃል ፤ ያዩ ፡ ዘንድ ፡
ዓይን ፡ አላቸው ፡ እነርሱም ፡ አያዩም ፥ ይሰ
ሙም ፡ ዘንድ ፡ ጆሮ ፡ አላቸው ፡ እነርሱም ፡
አይሰሙም ፤ እነርሱ ፡ ዓመፀኛ ፡ ቤት ፡ ናቸ
፫ ውና ። አንተም ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ የስደ
ተኛ ፡ እቃ ፡ አዘጋጅ ፡ በፊታቸውም ፡ ቀን ፡
ለቀን ፡ ተማረክ ፥ በፊታቸውም ፡ ከስፍራ ፡ ወደ ፡
ሌላ ፡ ስፍራ ፡ ተማርከህ ፡ ሂድ ፤ እነርሱም ፡ ዓመ
ፀኛ ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ምናልባት ፡ ያስተውሉ ፡
፬ ይሆናል ። ቀን ፡ ለቀንም ፡ በፊታቸው ፡ እቃ
ህን ፡ እንደ ፡ ስደተኛ ፡ እቃ ፡ አውጣው ፥ በማ
ታም ፡ ጊዜ ፡ በፊታቸው ፡ ስደተኞች ፡ እንደሚ
፭ ወጡ ፡ እንዲሁ ፡ ውጣ ። በፊታቸውም ፡ ግን
፮ ቡን ፡ ንደል ፡ በእርሱም ፡ አውጣ ። ለእስራኤ
ልም ፡ ቤት ፡ ምልክት ፡ አድርጌሃለሁና ፡ በፊ
ታቸው ፡ በጫንቃህ ፡ ላይ ፡ አንግተው ፥ በጨ
ለማም ፡ ተሸክመህ ፡ ውጣ ፤ ምድሪቱንም ፡ እን
፯ ዳታይ ፡ ፊትህን ፡ ሸፍን ። እንዳዘዘኝም ፡ አደረ
ግሁ ፤ ቀን ፡ ለቀንም ፡ እቃዬን ፡ እንደ ፡ ስደተኛ ፡
እቃ ፡ አወጣሁ ፥ በማታም ፡ ጊዜ ፡ ግንቡን ፡
በእጄ ፡ ነደልሁ ፥ በጨለማም ፡ አወጣሁት ፡
በፊታቸውም ፡ በጫንቃዬ ፡ ላይ ፡ አንግቼ ፡ ተሸ
ከምሁት ።

፰ በነጋውም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡
፱ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡
ሆይ ፥ ዓመፀኛ ፡ ቤት ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡—
የምታደርገው ፡ ምንድር ፡ ነው ? አላሉህምን ?
፲ አንተም ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡

ይላል ፡— ይህ ፡ ሸክም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በሚ
ኖረው ፡ አለቃ ፡ ላይ ፡ በመካከላቸውም ፡ በሚ
ኖሩት ፡ በእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነው ፡
፲፩ በላቸው ፡ ደግሞም ፡— እኔ ፡ ምልክታችሁ ፡
ነኝ ፤ እኔ ፡ እንዳደረግሁ ፡ እንዲሁ ፡ ይደረግባ
ቸዋል ፥ እነርሱም ፡ በስደት ፡ ወደ ፡ ምርኮ ፡
፲፪ ይሄዳሉ ፡ በል ። በመካከላቸውም ፡ የሚኖረው ፡
አለቃ ፡ በጫንቃው ፡ ላይ ፡ አንግቶ ፡ በጨለማ ፡
ይወጣል ፡ በዚያ ፡ ያወጡ ፡ ዘንድ ፡ ግንቡን ፡
ይነድላሉ ፥ በዓይኑም ፡ ምድርን ፡ እንዳያይ ፡
፲፫ ፊቱን ፡ ይሸፍናል ። መረቤንም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡
እዘረጋለሁ ፡ በወጥመዴም ፡ ይያዛል ፥ ወደ ፡
ከለዳውያንም ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ አመ
ጣዋለሁ ፤ ሆኖም ፡ አያያትም ፡ በዚያም ፡ ይሞ
፲፬ ታል ። ሊረዱትም ፡ በዙሪያው ፡ ያሉትን ፡
ሁሉ ፡ ጭፍሮቹንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ነፋሳት ፡
ሁሉ ፡ እበትናቸዋለሁ ፤ በኋላቸውም ፡ ሰይፍ ፡
፲፭ እመዝዛለሁ ። በአሕዛብም ፡ መካከል ፡ በበተን
ኋቸው ፡ ጊዜ ፥ በአገሮችም ፡ በዘራኋቸው ፡
ጊዜ ፥ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡
፲፮ ያውቃሉ ። በሚሄዱባቸውም ፡ አሕዛብ ፡ መካ
ከል ፡ ርኵሰታቸውን ፡ ሁሉ ፡ ይናገሩ ፡ ዘንድ ፡
ከሰይፍና ፡ ከራብ ፡ ከቸነፈርም ፡ ጥቂቶች ፡ ሰዎ
ችን ፡ ከእነርሱ ፡ አስቀራለሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።

፲፯ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፲፰ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ እን
ጀራህን ፡ በድንጋጤ ፡ ብላ ፡ ውኃህንም ፡ በመ
፲፱ ንቀጥቀጥና ፡ በኀዘን ፡ ጠጣ ፤ ለምድሪቱም ፡
ሕዝብ ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በኢየሩሳሌም ፡
ስለሚኖሩ ፡ ስለ ፡ እስራኤልም ፡ ምድር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፡— ስለሚኖሩበት ፡ ሁሉ ፡ ግፍ ፡
ምድሪቱ ፡ ከነሞላዋ ፡ ትጠፋ ፡ ዘንድ ፡ እንጀራ
ቸውን ፡ በችግር ፡ ይበላሉ ፡ ውኃቸውንም ፡
፳ በድንጋጤ ፡ ይጠጣሉ ። ሰዎች ፡ የሚኖሩብ
ቸው ፡ ከተሞች ፡ በድማ ፡ ይሆናሉ ፡ ምድሪ
ቱም ፡ ውድማ ፡ ትሆናለች ፤ እኔም ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ፡ በላቸው ።

፳፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፳፪ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ በእ
ስራኤል ፡ ምድር ፡— ዘመኑ ፡ ረዝሞአል ፡ ራእ
ዩም ፡ ሁሉ ፡ ጠፍቶአል ፡ የምትሉት ፡ ምሳሌ ፡
፳፫ ምንድር ፡ ነው ? ስለዚህ ፡ እንዲህ ፡ በላቸው ፡—
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ይህን ፡
ምሳሌ ፡ አስቀረዋለሁ ፡ በእስራኤልም ፡ ዘንድ ፡
ደግሞ ፡ ምሳሌ ፡ አድርገው ፡ አይናገሩትም ፤
አንተ ፡ ግን ፡— ዘመኑና ፡ የራእዩ ፡ ሁሉ ፡ ነገር ፡
፳፬ ቀርቦአል ፡ በላቸው ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በእ
ስራኤል ፡ ቤት ፡ መካከል ፡ ከንቱ ፡ ራእይና ፡
፳፭ ውሸተኛ ፡ ምዋርት ፡ አይሆንም ። እኔ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ነኝ ፤ እናገራለሁ ፡ የምናገረውም ፡ ቃል ፡
ይፈጸማል ፥ ደግሞም ፡ አይዘገይም ፤ እናንተ ፡
ዓመፀኛ ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ በዘመናችሁ ፡ ቃሌን ፡
እናገራለሁ ፡ እፈጽመውማለሁ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ።

፳፮ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡
፳፯ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ እነሆ ፥
የእስራኤል ፡ ቤት ፡— ይህች ፡ የሚያያት ፡ ራእይ ፡
ለብዙ ፡ ዘመን ፡ ናት ፥ እርሱም ፡ ለሩቅ ፡ ወራት ፡
፳፰ ትንቢት ፡ ይናገራል ፡ ይላሉ ። ስለዚህ ፡ በላ
ቸው ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
የምናገረው ፡ ቃል ፡ ይፈጸማል ፡ እንጂ ፡ ከቃሌ ፡
ሁሉ ፡ ደግሞ ፡ የሚዘገይ ፡ የለም ፥ ይላል ፡ እግ
ዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፪ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ትን
ቢት ፡ በሚናገሩ ፡ በእስራኤል ፡ ነቢያት ፡ ላይ ፡
ትንቢት ፡ ተናገር ፥ ከገዛ ፡ ልባቸውም ፡ ትን
ቢት ፡ የሚናገሩትን ፡— የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
፫ ስሙ ፡ በላቸው ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— ምንምን ፡ ሳያዩ ፡ የገዛ ፡ መንፈሳቸ
ውን ፡ ለሚከተሉ ፡ ለሰነፎች ፡ ነቢያት ፡ ወዮላ
፬ ቸው ! እስራኤል ፡ ሆይ ፥ ነቢያትህ ፡ በምድረ ፡
፭ በዳ ፡ እንደሚኖሩ ፡ ቀበሮች ፡ ናቸው ። ወደ ፡ ተሰ
በረው ፡ ቅጥር ፡ አልወጣችሁም ፥ በእግዚአብ
ሔርም ፡ ቀን ፡ በሰልፍ ፡ ትቆሙ ፡ ዘንድ ፡ ለእስ
፮ ራኤል ፡ ቤት ፡ ቅጥር ፡ አልሠራችሁም ። እግ
ዚአብሔር ፡ ሳይልካቸው ፡— እግዚአብሔር ፡
ይላል ፡ የሚሉ ፡ ሰዎች ፡ ከንቱ ፡ ነገርንና ፡ ውሸ
ተኛ ፡ ምዋርትን ፡ አይተዋል ፤ ቃሉም ፡ ይጠና ፡
፯ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ አስደርገዋል ። እኔም ፡ ሳልና
ገር ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ብሎአል ፡
ስትሉ ፥ ከንቱ ፡ ራእይን ፡ ያያችሁ ፡ ውሸተኛ
ንም ፡ ምዋርት ፡ የተናገራችሁ ፡ አይደላችሁ
ምን ?

፰ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— ከንቱ ፡ ነገርን ፡ ስለ ፡ ተናገራችሁ ፡
ውሸተኛ ፡ ራእይንም ፡ ስላያችሁ ፥ ስለዚህ ፥
እነሆ ፥ እኔ ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ነኝ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡
፱ እግዚአብሔር ። እጄም ፡ ከንቱ ፡ ራእይን ፡ በሚ
ያዩ ፥ በውሸትም ፡ በሚያምዋርቱ ፡ ነቢያት ፡
ላይ ፡ ትሆናለች ፤ እነርሱም ፡ በሕዝቤ ፡ ማኅበር ፡
ውስጥ ፡ አይገኙም ፥ በእስራኤልም ፡ ቤት ፡
መጽሐፍ ፡ አይጻፉም ፥ ወደ ፡ እስራኤልም ፡
ምድር ፡ አይገቡም ፤ እኔም ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
፲ ሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ። ሰላም ፡ ሳይ
ኖር ፡— ሰላም ፡ እያሉ ፡ ሕዝቤን ፡ አታልለዋ
ልና ፤ አንዱም ፡ ሰው ፡ ቅጥር ፡ ሲሠራ ፥ እነሆ ፥
፲፩ ገለባ ፡ በሌለበት ፡ ጭቃ ፡ ይመርጉታልና ፡ ገለባ ፡
በሌለበት ፡ ጭቃ ፡ ለሚመርጉት ፡ ሰዎች ፡— ይወ
ድቃል ፡ በላቸው ። የሚያሰጥም ፡ ዝናብ ፡ ይዘን
ባል ፥ ታላቅም ፡ የበረዶ ፡ ድንጋይ ፡ ይወድቃል ፥
፲፪ ዐውሎ ፡ ነፋስም ፡ ይሰነጣጥቀዋል ። እነሆ ፥
ግንቡ ፡ በወደቀ ፡ ጊዜ ፡— የመረጋችሁት ፡ ጭቃ ፡
፲፫ ወዴት ፡ አለ ? አይሉአችሁምን ? ስለዚህ ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በመዓቴ ፡

በዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ እሰነጣጥቀዋለሁ ፥ ያጠፋ
ውም ፡ ዘንድ ፡ በቍጣዬ ፡ የሚያሰጥም ፡ ዝናብ ፥
በመዓቴም ፡ ታላቅ ፡ የበረዶ ፡ ድንጋይ ፡ ይወር
፲፬ ዳል ። ገለባም ፡ በሌለበት ፡ ጭቃ ፡ የመረጋች
ሁትን ፡ ቅጥር ፡ አፈርሳለሁ ፡ ወደ ፡ ምድርም ፡
እጥለዋለሁ ፥ መሠረቱም ፡ ይታያል ። እርሱም ፡
ይናዳል ፡ በመካከሉም ፡ ትጠፋላችሁ ፤ እኔም ፡
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ።
፲፭ መዓቴንም ፡ በግንቡ ፡ ላይ ፡ ገለባም ፡ በሌለበት ፡
ጭቃ ፡ በመረጉት ፡ ላይ ፡ እፈጽማለሁ ፤ እኔም ፦
ግንቡና ፡ መረጊዎቹ ፡ የሉም ፡ እላችኋለሁ ።
፲፮ እነርሱም ፡ ስለ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ትንቢት ፡ የሚ
ናገሩ ፡ የሰላምን ፡ ራእይ ፡ የሚያዩላት ፡ የእስራ
ኤል ፡ ነቢያት ፡ ናቸው ፥ ሰላምም ፡ የለም ፥ ይላል ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፲፯ አንተም ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ከገዛ ፡ ልባ
ቸው ፡ ትንቢት ፡ በሚናገሩ ፡ በሕዝብህ ፡ ሴቶች ፡
ልጆች ፡ ላይ ፡ ፊትህን ፡ አድርግ ፤ ትንቢትም ፡
፲፰ ተናገርባቸው ፥ እንዲህም ፡ በል ፦ ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ነፍስን ፡ ለማጥ
መድ ፡ ለእጅ ፡ ድጋፍ ፡ ሁሉ ፡ መከዳ ፡ ለሚሰፉ ፡
ለሰውም ፡ ሁሉ ፡ ራስ ፡ እንደ ፡ እየቁመቱ ፡ ሽፋን ፡
ለሚሠሩ ፡ ሴቶች ፡ ወዮላቸው ፤ የሕዝቤንም ፡
ነፍስ ፡ ብታጠምዱ ፡ በውኑ ፡ ነፍሳችሁን ፡ ታድ
፲፱ ናላችሁን ? ውሸታችሁን ፡ ለሚሰሙት ፡ ሕዝቤ ፡
እየዋሻችሁ ፡ ሞት ፡ የማይገባቸውን ፡ ነፍሳት ፡
ትገድሉ ፡ ዘንድ ፡ በሕይወትም ፡ መኖር ፡ የማይ
ገባቸውን ፡ ነፍሳት ፡ በሕይወት ፡ ታኖሩ ፡ ዘንድ ፡
ስለ ፡ ጭብጥ ፡ ገብስና ፡ ስለ ፡ ቍራሽ ፡ እንጀራ ፡
በሕዝቤ ፡ ዘንድ ፡ አርክሳችሁኛል ።

፳ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፦ እነሆ ፥ እኔ ፡ ነፍሳትን ፡ እንደ ፡ ወፍ ፡
በምታጠምዱበት ፡ በመከዳችሁ ፡ ላይ ፡ ነኝ ፥
ከክንዳችሁም ፡ ወስጄ ፡ እቀድዳታለሁ ፥ እንደ ፡
ወፍም ፡ የምታጠምዱአቸውን ፡ ነፍሳት ፡ እለ
፳፩ ቅቃለሁ ። ሽፋኖቻችሁን ፡ ደግሞ ፡ እቀድዳ
ለሁ ፡ ሕዝቤንም ፡ ከእጃችሁ ፡ አድናለሁ ፥ ከዚ
ያም ፡ ወዲያ ፡ በእጃችሁ ፡ ለመታደን ፡ አይሆ
ኑም ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡
፳፪ ታውቃላችሁ ። እኔም ፡ ያላሳዘንሁትን ፡ የጻድ
ቁን ፡ ልብ ፡ በውሸት ፡ አሳዝናችኋልና ፥ በሕይ
ወትም ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ ከክፉ ፡ መንገድ ፡ እንዳ
ይመለስ ፡ የኃጢአተኛውን ፡ እጅ ፡ አበርትታች
፳፫ ኋልና ፡ ስለዚህ ፡ ከንቱን ፡ ራእይ ፡ እንግዲህ ፡
አታዩም ፡ ምዋርትንም ፡ አታምዋርቱም ፥ ሕዝ
ቤንም ፡ ከእጃችሁ ፡ አድናለሁ ፤ እኔም ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ ከእስራኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡ አያሌ ፡ ሰዎች ፡
ወደ ፡ እኔ ፡ መጥተው ፡ በፊቴ ፡ ተቀመጡ ።
፪ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡
፫ ሲል ፡ መጣ ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ እነዚህ ፡
ሰዎች ፡ ጣዖቶቻቸውን ፡ በልባቸው ፡ አኑረዋል ፡
የበደላቸውንም ፡ መቅሠፍት ፡ በፊታቸው ፡
አቁመዋል ፤ እኔስ ፡ ከእነርሱ ፡ ልጠየቅን ?
፬፡፭ ስለዚህ ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፦ ሁሉም ፡ በጣዖቶቻቸው ፡ ከእኔ ፡ ተለ
ይተዋልና ፡ የእስራኤልን ፡ ቤት ፡ በልባቸው ፡
እይዝ ፡ ዘንድ ፡ ከእስራኤል ፡ ቤት ፡ ጣዖቶቹን ፡
በልቡ ፡ የሚያኖር ፥ የበደሉንም ፡ መቅሠፍት ፡
በፊቱ ፡ የሚያቆም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡
በመጣ ፡ ጊዜ ፥ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡
ጣዖታቱ ፡ ብዛት ፡ እመልስለታለሁ ፡ ብለህ ፡ ንገ
ራቸው ።

፮ ስለዚህ ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ እንዲህ ፡ በል ፦
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ንስሐ ፡
ግቡ ፡ ከጣዖቶቻችሁም ፡ ተመለሱ ፥ ፊታችሁ
፯ ንም ፡ ከርኵሰታችሁ ፡ ሁሉ ፡ መልሱ ። ከእስራ
ኤልም ፡ ቤት ፥ በእስራኤልም ፡ ዘንድ ፡ ከሚቀ
መጡ ፡ መጻተኞች ፡ የሚሆን ፥ ከእኔ ፡ ተለይቶ ፡
ጣዖቶቹን ፡ በልቡ ፡ የሚያኖር ፥ የበደሉንም ፡
መቅሠፍት ፡ በፊቱ ፡ የሚያቆም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፥
ስለ ፡ እኔ ፡ ይጠይቅ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡
በመጣ ፡ ጊዜ ፥ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ በራሴ ፡
፰ እመልስለታለሁ ፤ ፊቴንም ፡ በዚያ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡
አደርጋለሁ ፡ ምልክትና ፡ ምሳሌም ፡ አደርገዋ
ለሁ ፡ ከሕዝቤም ፡ መካከል ፡ አጠፋዋለሁ ፤
እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታው
፱ ቃላችሁ ። ነቢዩም ፡ ቢታለል ፡ ቃልንም ፡ ቢና
ገር ፥ ያንን ፡ ነቢይ ፡ ያታለልሁ ፡ እኔ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ነኝ ፥ እጄንም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ እዘረ
ጋለሁ ፡ ከሕዝቤም ፡ ከእስራኤል ፡ መካከል ፡
፲ አጠፋዋለሁ ። ኃጢአታቸውን ፡ ይሸከማሉ ፡
እንደሚጠይቀውም ፡ ሰው ፡ ኃጢአት ፡ እንዲሁ ፡
፲፩ የነቢዩ ፡ ኃጢአት ፡ ይሆናል ። ይኸውም ፡ የእ
ስራኤል ፡ ቤት ፡ ደግሞ ፡ ከእኔ ፡ ርቀው ፡ እንዳ
ይስቱ ፡ በኃጢአታቸውም ፡ ሁሉ ፡ እንዳይረክሱ ፡
ነው ፤ እነርሱም ፡ ሕዝብ ፡ ይሆኑኛል ፡ እኔም ፡
አምላክ ፡ እሆናቸዋለሁ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚ
አብሔር ።

፲፪ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፲፫ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥
ምድር ፡ በማመፅ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ኃጢአት ፡ ስት
ሠራ ፥ እኔም ፡ እጄን ፡ ስዘረጋባት ፡ የእንጀራ
ዋንም ፡ በትር ፡ ስሰብር ፡ ራብን ፡ ስሰድድባት ፡
ሰውንና ፡ እንስሳውንም ፡ ከእርስዋ ፡ ሳጠፋ ፥
፲፬ እነዚህ ፡ ሦስት ፡ ሰዎች ፥ ኖኅና ፡ ዳንኤል ፡
ኢዮብም ፥ ቢኖሩባት ፡ በጽድቃቸው ፡ የገዛ ፡
ነፍሳቸውን ፡ ብቻ ፡ ያድናሉ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡
፲፭ እግዚአብሔር ። ክፉዎቹን ፡ አራዊት ፡ በም
ድር ፡ ባሳልፍ ፡ እነርሱም ፡ ልጆችዋን ፡ ቢያ
ጠፉ ፡ ስለ ፡ አራዊትም ፡ ማንም ፡ እንዳያልፍ
፲፮ ባት ፡ በድማ ፡ ብትሆን ፥ እነዚህ ፡ ሦስት ፡ ሰዎች ፡
ቢኖሩባት ፥ እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ እነርሱ ፡ ብቻ
ቸውን ፡ ይድናሉ ፡ እንጂ ፡ ወንዶችንና ፡ ሴቶች ፡
ልጆቻቸውን ፡ አያድኑም ፥ ምድሪቱም ፡ በድማ ፡
ትሆናለች ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፲፯ ወይም ፡ በዚያች ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ ሰይፍ ፡ አምጥቼ ፡— ሰይፍ ፡ ሆይ ፥ በምድሪቱ ፡ ላይ ፡ እለፊ ፡ ብል ፥ ሰውንና ፡ እንስሳውንም ፡ ከእርስዋ ፡ ፲፰ ባጠፋ ፥ እነዚህ ፡ ሦስት ፡ ሰዎች ፡ ቢኖሩበት ፥ እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ እነርሱ ፡ ብቻቸውን ፡ ይድናሉ ፡ እንጂ ፡ ወንዶችንና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ አያድኑም ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ፲፱ ወይም ፡ በዚያች ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ ቸነፈር ፡ ብሰድድ ፡ ሰውንና ፡ እንስሳውንም ፡ ከእርስዋ ፡ አጠፋ ፡ ዘንድ ፡ መዓቴን ፡ በደም ፡ ባፈስስበት ፥ ፳ ኖኅና ፡ ዳንኤል ፡ ኢዮብም ፡ ቢኖሩበት ፥ እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ በጽድቃቸው ፡ ነፍሳቸውን ፡ ብቻ ፡ ያድናሉ ፡ እንጂ ፡ ወንዶችንና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ አያድኑም ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፳፩ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ይልቁንስ ፡ ሰውንና ፡ እንስሳን ፡ ከእርስዋ ፡ አጠፋ ፡ ዘንድ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ አራቱን ፡ ክፉ ፡ ፍርዶቼን ፥ ሰይፍንና ፡ ራብን ፡ ክፉዎችንም ፡ አውሬዎች ፡ ቸነፈርንም ፥ ስሰድድበት ! ፳፪ ነገር ፡ ግን ፥ እነሆ ፥ የሚያመልጡና ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆችን ፡ የሚያመጡ ፡ ይቀሩላታል ፤ እነሆ ፥ ወደ ፡ እናንተ ፡ ይወጣሉ ፡ እናንተም ፡ መንገዳቸውንና ፡ ሥራቸውን ፡ ታያላችሁ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ላይ ፡ ስላመጣሁት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ስላመጣሁበትም ፡ ነገር ፡ ፳፫ ሁሉ ፡ ትጽናናላችሁ ። መንገዳቸውንና ፡ ሥራቸውን ፡ ባያችሁ ፡ ጊዜ ፡ ያጽናኑአችኋል ፤ ያደረግሁበትንም ፡ ሁሉ ፡ በከንቱ ፡ እንዳላደረግሁበት ፡ ታውቃላችሁ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ፪ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ የወይን ፡ ግንድ ፥ በዱር ፡ ዛፎች ፡ መካከል ፡ ያለ ፡ የወይን ፡ አረግ ፥ ከዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ብል ፫ ጫው ፡ ምንድር ፡ ነው ? በውኑ ፡ ሥራ ፡ የሚሠራበትን ፡ እንጨት ፡ ከእርሱ ፡ ይወስዳሉን ? ወይስ ፡ ሰዎች ፡ ዕቃ ፡ የሚንጠለጠልበትን ፡ ፬ ኵላብ ፡ ከእርሱ ፡ ይወስዳሉን ? እነሆ ፥ ለመቃጠል ፡ በእሳት ፡ ላይ ፡ ተጥሎአል ፥ እሳቱም ፡ ሁለቱን ፡ ጫፎቹን ፡ በልቶአል ፥ መካከሉም ፡ ተቃጥሎአል ፤ በውኑ ፡ ለሥራ ፡ ይጠቅማልን? ፭ እነሆ ፥ ደህና ፡ ሳለ ፡ ለሥራ ፡ ካልጠቀመ ፥ ይልቁንስ ፡ እሳት ፡ ከበላው ፡ እርሱም ፡ ከተቃጠለ ፡ በኋላ ፡ እንዴት ፡ ሥራ ፡ ይሠራበታል ? ፮ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በዱር ፡ ዛፎች ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ የወይን ፡ ግንድ ፡ እሳት ፡ ይበላው ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ሰጠሁት ፥ እንዲሁ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩ ፯ ትን ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣለሁ ። ፊቴንም ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ አደርጋለሁ ፤ ከእሳትም ፡ ይወጣሉ ፥ እሳት ፡ ግን ፡ ይበላቸዋል ፤ ፊቴንም ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ባደረግሁ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ። ፰ ዓመፅን ፡ አድርገዋልና ፡ ምድሪቱን ፡ ባድማ ፡ አደርጋለሁ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን ፪ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ለኢ ፫ የሩሳሌም ፡ ርኵሰትዋን ፡ አስታውቃት ፥ እንዲህም ፡ በል ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለኢየሩሳሌም ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ዘርሽና ፡ ትውልድሽ ፡ ከከነዓን ፡ ምድር ፡ ነው ፤ አባትሽ ፡ አሞራዊ ፡ ነበረ ፡ እናትሽም ፡ ኬጢያዊት ፡ ነበረች ። ፬ በተወለድሽ ፡ ጊዜ ፡ በዚያው ፡ ቀን ፡ እትብትሽ ፡ አልተቈረጠም ፡ ንጹሕም ፡ ትሆኚ ፡ ዘንድ ፡ በውኃ ፡ አልታጠብሽም ፥ በጨውም ፡ አልተቀባሽም ፡ በጨርቅም ፡ አልተጠቀለልሽም ። ፭ በተወለድሽበት ፡ ቀን ፡ ከሰውነትሽ ፡ ጕስቍልና ፡ የተነሣ ፡ በሜዳ ፡ ላይ ፡ ተጣልሽ ፡ እንጂ ፡ ከዚህ ፡ አንዳች ፡ ይደረግልሽ ፡ ዘንድ ፡ ዓይን ፡ አልራራልሽም ፥ ማንም ፡ አላዘነልሽም ።

፮ በአንቺም ፡ ዘንድ ፡ ባለፍሁ ፡ ጊዜ ፡ በደምሽም ፡ ውስጥ ፡ ተለውሰሽ ፡ ባየሁሽ ፡ ጊዜ ፡— በደምሽ ፡ እንዳለሽ ፡ በሕይወት ፡ ኑሪ ፡ አልሁሽ ፤ አዎን ፡— በደምሽ ፡ እንዳለሽ ፡ በሕይወት ፡ ኑሪ ፡ አልሁሽ ። ፯ በእርሻ ፡ ላይ ፡ እንዳለ ፡ ቡቃያ ፡ አበዛሁሽ ፥ አንቺም ፡ አደግሽ ፡ ታላቅም ፡ ሆንሽ ፥ በእጅጉም ፡ አጌጥሽ ፤ ጡቶችሽም ፡ አጐጠጐጡ ፡ ጠጕርሽም ፡ አደገ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ዕርቃንሽን ፡ ሆንሽ ፥ ተራቍተሽም ፡ ነበርሽ ። ፰ በአንቺ ፡ ዘንድ ፡ ባለፍሁና ፡ ባየሁሽ ፡ ጊዜ ፥ እነሆ ፥ ጊዜሽ ፡ የፍቅር ፡ ጊዜ ፡ ነበረ ፤ እኔም ፡ መጐናጸፊያዬን ፡ በላይሽ ፡ ዘረጋሁ ፡ ኀፍረተ ፡ ሥጋሽንም ፡ ከደንሁ ፤ ማልሁልሽም ፡ ከአንቺም ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ገባሁ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥ አንቺም ፡ ለእኔ ፡ ሆንሽ ። ፱ በውኃም ፡ አጠብሁሽ ፡ ከደምሽም ፡ አጠራሁሽ ፡ በዘይትም ፡ ቀባሁሽ ። ፲ ወርቀ ፡ ዘቦም ፡ አለበስሁሽ ፡ በአቆስጣ ፡ ቁርበትም ፡ ጫማ ፡ አደረግሁልሽ ፤ በጥሩ ፡ በፍታ ፡ አስታጠቅሁሽ ፡ በሐርም ፡ ከደንሁሽ ። ፲፩ በጌጥም ፡ አስጌጥሁሽ ፡ በእጅሽም ፡ ላይ ፡ አንባር ፡ በአንገትሽም ፡ ላይ ፡ ድሪ ፡ አደረግሁልሽ ። ፲፪ በአፍንጫሽም ፡ ቀለበት ፡ በጆሮሽም ፡ ጕትቻ ፡ በራስሽም ፡ ላይ ፡ የክብር ፡ አክሊል ፡ አደረግሁ ። ፲፫ በወርቅና ፡ በብር ፡ አጌጥሽ ፥ ልብስሽም ፡ ጥሩ ፡ በፍታና ፡ ሐር ፡ ወርቀ ፡ ዘቦም ፡ ነበረ ፤ አንቺም ፡ መልካምን ፡ ዱቄትና ፡ ማርን ፡ ዘይትንም ፡ በላሽ ፤ እጅግ ፡ በጣም ፡ ውብ ፡ ሆንሽ ፡ ለመንግሥትም ፡ ደረስሽ ። ፲፬ ባንቺ ፡ ላይ ፡ ካኖርኋት ፡ ከክብሬ ፡ የተነሣ ፡ ውበትሽ ፡ ፍጹም ፡ ነበረና ፡ ዝናሽ ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ወጣ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፲፭ ነገር ፡ ግን ፡ በውበትሽ ፡ ታምነሻል ፡ ስለ ፡ ዝናሽም ፡ አመንዝረሻል ፡ ምንዝርናሽንም ፡ ከመን

፲፮ ገድ ፡ አላፊ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ አበዛሽ ። ከልብስ
ሽም ፡ ወስደሽ ፡ በኮረብቶች ፡ ላይ ፡ በዝንጕር
ጕር ፡ ልብስ ፡ ያስጌጥሽቸውን ፡ መስገጃች ፡ ለራ
ስሽ ፡ ሠራሽ ፡ በዚያም ፡ ገለሞትሽ ፤ እንዲህም ፡
ያለ ፡ ነገር ፡ ከአሁን ፡ በፊት ፡ አልነበረም ፥ ከእ
፲፯ ንግዲህም ፡ ወዲያ ፡ አይሆንም ። ከሰጠሁሽም ፡
ከወርቄና ፡ ከብሬ ፡ የተሠራውን ፡ የክብርሽን ፡
ዕቃ ፡ ወስደሽ ፡ የወንድ ፡ ምስሎች ፡ ለራስሽ ፡
፲፰ አድርገሻል ፡ አመንዝረሽባቸውማል ። ወርቀ ፡
ዘበውን ፡ ልብስሽንም ፡ ወስደሽ ፡ ደረብሽላ
ቸው ፥ ዘይቴንና ፡ ዕጣኔንም ፡ በፊታቸው ፡ አኖ
፲፱ ርሽ ። የሰጠሁሽንም ፡ እንጀራዬን ፡ ያበላሁሽ
ንም ፡ መልካሙን ፡ ዱቄትና ፡ ዘይቱን ፡ ማሩ
ንም ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ አድርገሽ ፡ በፊታቸው ፡
አኖርሽ ፥ እንዲሁም ፡ ሆኖአል ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡
፳ እግዚአብሔር ። ለእኔም ፡ የወለድሻቸውን ፡
ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆችሽን ፡ ወስደሽ ፡
፳፩ መብል ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ሠዋሽላቸው ። ልጆ
ቼን ፡ አረድሽ ፤ ለእነርሱም ፡ በእሳት ፡ በኩል ፡
አሳልፈሽ ፡ ሰጠሽ ፤ በውኑ ፡ ግልሙትናሽ ፡
፳፪ ጥቂት ፡ ነውን ? በርኵስነትሽና ፡ በግልሙት
ናሽ ፡ ሁሉ ፡ ዕርቃንሽን ፡ ሆነሽ ፡ ተራቍተሽም ፡
ሳለሽ ፡ በደምሽም ፡ ተለውሰሽ ፡ ሳለሽ ፡ የሕፃን
ነትሽን ፡ ወራት ፡ አላሰብሽም ።

፳፫ ወዮ ! ወዮልሽ ! ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
፳፬ ሔር ፤ ከክፋትሽም ፡ ሁሉ ፡ በኋላ ፡ የምንዝርናን ፡
ስፍራ ፥ በየአደባባዩም ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ በታን ፡
፳፭ ለራስሽ ፡ ሠራሽ ። በየመንገዱ ፡ ራስ ፡ ከፍ ፡
ያለውን ፡ በታሽን ፡ ሠራሽ ፥ ውበትሽንም ፡
አረከስሽ ፥ ለመንገድ ፡ አላፊም ፡ ሁሉ ፡ እግር
ሽን ፡ ገለጥሽ ፡ ግልሙትናሽንም ፡ አበዛሽ ።
፳፮ ሥጋቸውም ፡ ከወፈረ ፡ ከጐረቤቶችሽ ፡ ከግብጻ
ውያን ፡ ጋር ፡ አመነዘርሽ ፥ እኔንም ፡ ታስቈጭ ፡
፳፯ ዘንድ ፡ ግልሙትናሽን ፡ አበዛሽ ። ስለዚህ ፥
እነሆ ፥ እጄን ፡ በአንቺ ፡ ላይ ፡ ዘርግቻለሁ ፡
ድርጎሽንም ፡ አጕድያለሁ ፤ ለሚጠሉሽም ፡
ከክፉ ፡ መንገድሽ ፡ የተነሣ ፡ ለሚያፍሩ ፡ ለፍል
ስጥኤም ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ፈቃድ ፡ አሳልፌ ፡
፳፰ ሰጥቼሻለሁ ። አልጠገብሽምና ፡ ከአሦራውያን ፡
ጋር ፡ ደግሞ ፡ ገለሞትሽ ፡ ከዚህም ፡ ጋር ፡ ገና ፡
፳፱ አልጠገብሽም ። እስከ ፡ ነጋዴዎች ፡ ምድር ፡
እስከ ፡ ከላውዴዎን ፡ ድረስ ፡ ግልሙትናሽን ፡
አበዛሽ ። ከዚህም ፡ ጋር ፡ ገና ፡ አልጠገብሽም ።

፴ የማታፍረውን ፡ የጋለሞታን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡
ሠርተሻልና ፡ ልብሽ ፡ ምንኛ ፡ ደካማ ፡ ነው ?
፴፩ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። በየመንገዱ ፡
ራስ ፡ የምንዝርናሽን ፡ ስፍራ ፡ ሠርተሻል ፡ በየአ
ደባበዩም ፡ ከፍ ፡ ያለውን ፡ በታሽን ፡ አድርገ
ሻል ። ዋጋዋን ፡ እንደምትንቅ ፡ እንደ ፡ ጋለሞታ ፡
፴፪ አልሆንሽም ። በባልዋ ፡ ፋንታ ፡ ሌሎችን ፡
ተቀብላ ፡ የምታመነዝር ፡ ሴትን ፡ ትመስያለሽ ።
፴፫ ለጋለሞቶች ፡ ሁሉ ፡ ዋጋ ፡ ይሰጡአቸዋል ፤
አንቺ ፡ ግን ፡ ለውሽሞችሽ ፡ ሁሉ ፡ ዋጋ ፡ ትሰ
ጫለሽ ፥ ከአንቺም ፡ ጋር ፡ ለማመንዘር ፡ በዙሪ
ያሽ ፡ ይገቡብሽ ፡ ዘንድ ፡ መማለጃ ፡ ትሰጫቸዋ
፴፬ ለሽ ። ግልሙትናሽ ፡ ከሌሎች ፡ ሴቶች ፡ ግል
ብጥ ፡ ነው ፤ ማንም ፡ ለግልሙትና ፡ የሚከተ
ልሽ ፡ የለም ፤ ዋጋ ፡ ሳይሰጥሽ ፡ አንቺ ፡ ዋጋ ፡
በመስጠትሽ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ልዩ ፡ ሆነሻል ።

፴፭ ስለዚህ ፥ ጋለሞታ ፡ ሆይ ፥ የእግዚአብሔርን ፡
፴፮ ቃል ፡ ስሚ ። ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— ከውሽሞችሽ ፡ ጋር ፡ ባደረግሽው ፡
በግልሙትናሽ ፡ ርኵሰትሽ ፡ ስለ ፡ ፈሰሰ ፡ ኀፍ
ረት ፡ ሥጋሽም ፡ ስለ ፡ ተገለጠ ፥ ስለ ፡ ርኵሰት
ሽም ፡ ጣዖታት ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ሰጠሻቸውም ፡
፴፯ ስለ ፡ ልጆች ፡ ደም ፥ ስለዚህ ፥ እነሆ ፥ ከእነ
ርሱ ፡ ጋር ፡ ደስ ፡ ያለሽን ፡ የወደድሻቸውንም ፡
ውሽሞችሽ ፡ ሁሉ ፡ ከጠላሻቸው ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡
እሰበስባቸዋለሁ ፤ በአንቺ ፡ ላይ ፡ በዙሪያሽ ፡
እሰበስባቸዋለሁ ፥ ኀፍረተ ፡ ሥጋሽንም ፡ ሁሉ ፡
እንዲያዩ ፡ በፊታቸው ፡ ኀፍረተ ፡ ሥጋሽን ፡
፴፰ እገልጣለሁ ። በአመንዝሮችና ፡ በደም ፡ አፍሳ
ሾች ፡ ላይ ፡ የሚፈረደውን ፡ ፍርድ ፡ እፈርድብ
ሻለሁ ፥ የመዓትንና ፡ የቅንዓትን ፡ ደምም ፡
፴፱ አመጣብሻለሁ ። በእጃቸውም ፡ አሳልፌ ፡ እሰ
ጥሻለሁ ፥ የምንዝርናሽንም ፡ ስፍራ ፡ ያፈር
ሳሉ ፡ ከፍ ፡ ያለውንም ፡ በታሽን ፡ ይገለብጣሉ ፤
ልብስሽንም ፡ ይገፉሻል ፡ የክብርሽንም ፡ ጌጥ ፡
ይወስዳሉ ፥ ዕርቃንሽን ፡ አድርገው ፡ ዕራቁት
፵ ሽን ፡ ይተዉሻል ። ጉባኤን ፡ ያመጡብሻል ፡
በድንጋይም ፡ ይወግሩሻል ፥ በሰይፋቸውም ፡
፵፩ ይወጉሻል ። ቤቶችሽንም ፡ በእሳት ፡ ያቃጥላሉ ፡
በብዙም ፡ ሴቶች ፡ ፊት ፡ በላይሽ ፡ ፍርድን ፡
ያደርጉብሻል ፤ ግልሙትናሽንም ፡ አስተውሻ
፵፪ ለሁ ፥ እንግዲህስ ፡ ዋጋ ፡ አትሰጭም ። መዓቴ
ንም ፡ በአንቺ ፡ ላይ ፡ እጨርሳለሁ ፡ ቅንዓቴም ፡
ከአንቺ ፡ ይርቃል ፥ እኔም ፡ ዝም ፡ እላለሁ ፡
፵፫ ደግሞም ፡ አልቈጣም ። የሕፃንነትሽን ፡ ወራት ፡
አላሰብሽምና ፥ በዚህም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አስቈጥ
ተሽኛልና ፡ ስለዚህ ፥ እነሆ ፥ እኔ ፡ ደግሞ ፡
መንገድሽን ፡ በራስሽ ፡ ላይ ፡ አመጣለሁ ፥ ይላል ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥ ሌላንም ፡ ነውር ፡ በርኵ
ሰትሽ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አትጨምሪም ።

፵፬ እነሆ ፥ በምሳሌ ፡ የሚናገር ፡ ሁሉ ፡— እንደ ፡
እናቲቱ ፡ እንዲሁ ፡ ሴት ፡ ልጂቱ ፡ ናት ፡ እያለ ፡
፵፭ ምሳሌ ፡ ይመስልብሻል ። አንቺ ፡ ባልዋንና ፡
ልጆችዋን ፡ የጠላሽ ፡ የእናትሽ ፡ ልጅ ፡ ነሽ ፤
አንቺም ፡ ባሎቻቸውንና ፡ ልጆቻቸውን ፡
የጠሉ ፡ የእኅቶችሽ ፡ እኅት ፡ ነሽ ፤ እናታችሁ ፡
ኬጢያዊት ፡ ነበረች ፡ አባታችሁም ፡ አሞራዊ ፡
፵፮ ነበረ ። ታላቂቱም ፡ እኅትሽ ፡ ከሴቶች ፡ ልጆ
ችዋ ፡ ጋር ፡ በስተ ፡ ግራሽ ፡ የምትቀመጥ ፡ ሰማ
ርያ ፡ ናት ፤ ታናሺቱም ፡ እኅትሽ ፡ ከሴቶች ፡
ልጆችዋ ፡ ጋር ፡ በስተ ፡ ቀኝሽ ፡ የምትቀመጥ ፡
፵፯ ሰዶም ፡ ናት ። አንቺ ፡ ግን ፡ በመንገዳቸው ፡ አልሄ
ድሽም ፡ እንደ ፡ ርኵሰታቸውም ፡ አላደረግሽም ፤
ያው ፡ ለአንቺ ፡ ጥቂት ፡ ነበረና ፡ በመንገድሽ ፡
ሁሉ ፡ ከእነርሱ ፡ የሚከፋ ፡ ርኵሰት ፡ አደረግሽ ።

፵፰ እኔ፡ሕያው፡ነኝና፡አንቺና፡ሴቶች፡ልጆችሽ፡
እንዳደረጋቸሁት፡እንዲሁ፡ሰዶምና፡ሴቶች፡
ልጆችዋ፡አላደረጉም÷ይላል፡ጌታ፡እግዚ
፵፱ አብሔር ። እነሆ÷የእኅትሽ፡የሰዶም፡ኃጢ
አት፡ይህ፡ነበረ፤ ትዕቢት፡እንጀራን፡መጥ
ገብ፡መዝለልና፡ሥራ፡መፍታት፡በእርስዋና፡
በሴቶች፡ልጆችዋ፡ነበረ÷የችግረኛውንና፡
፶ የድሀውንም፡እጅ፡አላጸናችም ። ኰርተው፡
ነበር፡በፊቴም፡ርኩስ፡ነገር፡አደረጉ፤ ስለ
፶፩ ዚህ፡በየሁ፡ጊዜ፡አጠፋኋቸው ። ሰማርያም፡
የኃጢአትሽን፡እኩሌታ፡አልሠራችም፤ አንቺ፡
ግን፡ከእኅቶችሽ፡ይልቅ፡ርኵሰትሽን፡አበዛሽ÷
በሠራሽም፡ርኵሰት፡ሁሉ፡አጸደቅሻቸው ።
፶፪ አሁንም፡ለእኅቶችሽ፡ስለ፡ፈረድሽ፡እፍረት
ሽን፡ተሸከሚ፤ ከእነርሱ፡የባሰ፡ኃጢአት፡
ሠርተሻልና፡ከአንቺ፡ይልቅ፡ጻድቃን፡ናቸው፤
እኅቶችሽንም፡ስለ፡አጸደቅሻቸው፡እፈሪ፡
፶፫ እፍረትሽንም፡ተሸከሚ ። ምርኮአቸውን÷
የሰዶምና፡የሴቶች፡ልጆችዋን፡ምርኮ÷የሰ
ማርያንና፡የሴቶች፡ልጆችዋንም፡ምርኮ÷
በመካከላቸውም፡ያሉትን፡የምርኮኞችሽን፡
፶፬ ምርኮ፡እመልሳለሁ፤ ስለ፡አጽናናሻቸው÷
እፍረትን፡ትሸከሚ፡ዘንድ፡ስለ፡አደረግሽ
፶፭ ውም፡ሁሉ፡ታፍሪ፡ዘንድ ። እኅቶችሽም፡
ሰዶምና፡ሴቶች፡ልጆችዋ፡ወደ፡ቀድሞ፡
ሁኔታቸው፡ይመለሳሉ÷ሰማርያና፡ሴቶች፡ልጆ
ችዋም፡ወደ፡ቀድሞ፡ሁኔታቸው፡ይመለ
ሳሉ÷አንቺና፡ሴቶች፡ልጆችሽም፡ወደ፡
፶፮ ቀድሞ፡ሁኔታችሁ፡ትመለሳላችሁ ። ክፋትሽ፡
ሳይገለጥ፡በትዕቢትሽ፡ቀን፡እኅትሽ፡ሰዶም፡
፶፯ በአፍሽ፡መተረቻ፡አልነበረችምን? አሁን፡ለሶ
ርያ፡ሴቶች፡ልጆችና፡ለጎረቤቶችዋ፡ሁሉ÷በዙ
ሪያሽም፡ለሚንቁሽ፡ለፍልስጥኤም፡ሴቶች፡
ልጆች፡እንደ፡እርስዋ፡መሰደቢያ፡ሆነሻል ።
፶፰ ምንዝርነትሽንና፡ርኵስነትሽን፡ተሸክመሻል÷
ይላል፡እግዚአብሔር ።

፶፱ ጌታ፡እግዚአብሔርም፡እንዲህ፡ይላል፡—
አንቺ፡ቃል፡ኪዳንን፡በማፍረስ፡መሐላን፡
የናቅሽ፡ሆይ÷አንቺ፡እንዳደረግሽ፡እኔ፡
፷ ደግሞ፡አደርግብሻለሁ ። ነገር፡ግን፡በሕፃንነ
ትሽ፡ወራት፡ከአንቺ፡ጋር፡ያደረግሁትን፡
ቃል፡ኪዳኔን፡አስበለሁ፡የዘላለምንም፡ቃል፡
፷፩ ኪዳን፡አጸናልሻለሁ ። እኅቶችሽንም፡ታላቂ
ቱንና፡ታናሺቱን፡በተቀበልሽ፡ጊዜ፡መንገ
ድሽን፡ታስቢያለሽ፡ታፍሪማለሽ፤ ለአንቺም፡
ልጆች፡ይሆኑ፡ዘንድ፡እሰጣቸዋለሁ÷ስለ፡
፷፪፡፷፫ ቃል፡ኪዳንሽ፡ግን፡አይደለም ። ስላደረግሽ
ውም፡ሁሉ፡ይቅር፡በልሁሽ፡ጊዜ÷ታስቢ፡
ዘንድ፡ታፍሪም፡ዘንድ፡ስለ፡እፍረትሽም፡
ደግሞ፡አፍሽን፡እንዳትከፍቺ÷ቃል፡ኪዳ
ኔን፡ከአንቺ፡ጋር፡አጸናለሁ፡እኔም፡እግዚ
አብሔር፡እንደ፡ሆንሁ፡ታውቂያለሽ÷ይላል፡
ጌታ፡እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ፡፲፯ ።

፩ የእግዚአብሔር፡ቃል፡ወደ፡እኔ፡እንዲህ፡
፪ ሲል፡መጣ፡— የሰው፡ልጅ፡ሆይ÷በእንቈቅ
ልሽ፡አጫውት፡ለእስራኤልም፡ቤት፡ምሳሌ፡
፫ ንገር÷እንዲህም፡በል፡— ጌታ፡እግዚአብሔር፡
እንዲህ፡ይላል፡— ታላቅ፡ክንፍ፡ረጅምም፡
ማርገብገቢያ፡ያለው፡ላባም፡የተሞላ÷መልከ፡
ዥንጕርጕር፡ታላቅ፡ንስር፡ወደ፡ሊባኖስ፡
፬ መጣ÷የዝግባንም፡ጫፍ፡ወሰደ ። ቀንበጡ
ንም፡ቀነጠበ፡ወደ፡ከነዓንም፡ምድር፡ወሰ
፭ ደው፡በነጋዶችም፡ከተማ፡አኖረው ። ከምድ
ርም፡ዘር፡ወሰደ፡በፍሬያማ፡እርሻ፡ተከለው፡
በብዙም፡ውኃ፡አጠገብ፡እንደ፡አኻያ፡ዛፍ፡
፮ አኖረው ። በበቀለም፡ጊዜ፡ቁመቱ፡ያጠረ፡
አረጉም፡ወደ፡እርሱ፡የሚመለስ፡ሥሩም፡
በበታቹ፡የነበረ፡ሰፊ፡ወይን፡ሆነ÷እንዲሁ፡
ወይን፡ሆነ፡አረግም፡ሰደደ፡ቀንበጥም፡
አወጣ ።

፯ ታላቅ፡ክንፍና፡ብዙ፡ላባም፡ያለው፡ሌላ፡
ታላቅ፡ንስር፡ነበረ፤ እነሆም÷ያጠጣው፡
ዘንድ፡ይህ፡ወይን፡ሥሩን፡ወደ፡እርሱ፡
አዘነበለ፡አረጉንም፡ከተተከለበት፡ከመደቡ፡
፰ ወደ፡እርሱ፡ሰደደ ። አረግም፡ያወጣ፡ፍሬም፡
ያፈራ፡የከበረም፡ወይን፡ይሆን፡ዘንድ፡በመ
ልካም፡መሬት፡ውስጥ፡በብዙም፡ውኃ፡አጠ
፱ ገብ፡ተተክሎ፡ነበር ። እንዲህም፡በል፡—
ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— በውኑ፡
ይከናወንለት፡ይሆንን? ይደርቅስ፡ዘንድ÷
አዲስ፡የበቀለውስ፡ቅጠሉ፡ይጠወልግ፡
ዘንድ፡ሥሩን፡አይነቅለውምን? ፍሬውንስ፡
አይለቅመውምን? ሥሩም፡የተነቀለው፡በብ
ርቱ፡ክንድና፡በብዙ፡ሕዝብ፡አይደለም ።
፲ ተተክሎስ÷እነሆ÷ይከናወንለት፡ይሆንን?
የምሥራቅ፡ነፋስ፡በገኘው፡ጊዜ፡ፈጽሞ፡
አይደርቅምን? በተተከለበት፡መደብ፡ላይ፡
ይደርቃል ።

፲፩ የእግዚአብሔርም፡ቃል፡ወደ፡እኔ፡እን
፲፪ ዲህ፡ሲል፡መጣ፡— ለዓመፀኛ፡ቤት፡— ይህ፡
ትርጓሜ፡ምን፡እንደ፡ሆነ፡አታውቁምን?
በላቸው ። እንዲህም፡ብለህ፡ንገራቸው፡—
እነሆ÷የባቢሎን፡ንጉሥ፡ወደ፡ኢየሩሳ
ሌም፡መጣ÷ንጉሥዋንና፡መኳንንቶችዋ
ንም፡ማረከ÷ወደ፡እርሱም፡ወደ፡ባቢሎን፡
፲፫ ወሰዳቸው ። ከመንግሥትም፡ዘር፡ወስዶ፡
ቃል፡ኪዳን፡ከእርሱ፡ጋር፡አደረገ፤ አማለ
፲፬ ውም÷የምድሪቱንም፡ኀያላን፡ወሰደ፤ ይኸ
ውም፡ቃል፡ኪዳኑን፡በመጠበቅ፡እንድት
ጸና፡እንጂ፡መንግሥቱ፡እንድትዋረድና፡
፲፭ ከፍ፡እንዳትል፡ነው ። እርሱ፡ግን፡በእርሱ፡
ላይ፡ሸፈተ፡ፈረሶችንና፡ብዙንም፡ሕዝብ፡
ይሰጡት፡ዘንድ፡መልእክተኞችን፡ወደ፡
ግብጽ፡ላከ ። በውኑ፡ይከናወንለት፡ይሆንን?

ይህንስ ፡ ያደረገ ፡ ያመልጣልን ? ቃል ፡ ኪዳን
፲፮ ንስ ፡ አፍርሶ ፡ ያመልጣልን ? እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡
ያነገሠውና ፡ መሐላውን ፡ የናቀበቱ ፥ ቃል ፡
ኪዳኑንም ፡ ያፈረሰበቱ ፡ ንጉሥ ፡ በሚኖርበት ፡
ስፍራ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በባቢሎን ፡ መካከል ፡
በእርግጥ ፡ ይሞታል ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአ
፲፯ ብሔር ። ብዙዎችን ፡ ነፍሳት ፡ ለማስወገድ ፡
አፈርን ፡ በደለደሉ ፡ ምሽግም ፡ በሠሩ ፡ ጊዜ ፥
ፈርዖን ፡ ከብዙ ፡ ሠራዊቱና ፡ ከታላቁ ፡ ጉባ
፲፰ ኤው ፡ ጋር ፡ በሰልፍ ፡ አይረዳውም ። ቃል ፡
ኪዳኑንም ፡ በማፍረስ ፡ መሐላውን ፡ ንቆአል ፤
እነሆም ፥ እጁን ፡ ሰጠ ፥ ይህንም ፡ ሁሉ ፡ አድ
፲፱ ርጎአል ፤ ስለዚህ ፡ አያመልጥም ። ስለዚህ ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እኔ ፡
ሕያው ፡ ነኝና ፡ የናቀውን ፡ መሐላዬን ፡ ያፈረ
ሰውንም ፡ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ አመ
፳ ጣለሁ ። መረቤንም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ እዘረጋ
ለሁ ፡ በወጥመድም ፡ ይያዛል ፥ ወደ ፡ ባቢሎ
ንም ፡ አመጣዋለሁ ፡ በእኔም ፡ ላይ ፡ ስላደረ
ገው ፡ ዓመፅ ፡ በዚያ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ እፋረዳ
፳፩ ለሁ ። ጭፍሮቹም ፡ ሁሉ ፡ በሰይፍ ፡ ይወድ
ቃሉ ፥ የቀሩትም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እየነፋሳቱ ፡
ይበተናሉ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተና
ገርሁ ፡ ታውቃላችሁ ።

፳፪ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ከረጅሙ ፡ ዝግባ ፡ ጫፍ ፡ ላይ ፡ ቀንበጥን ፡ ወስጄ ፡
አኖረዋለሁ ፤ ከጫፎቹ ፡ አንዱን ፡ ቀንበጥ ፡ እቀ
ነጥበዋለሁ ፤ በረጅምና ፡ በታላቅ ፡ ተራራም ፡
፳፫ ላይ ፡ እተክለዋለሁ ። ከፍ ፡ ባለው ፡ በእስራ
ኤል ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ እተክለዋለሁ ፥ ቅርንጫ
ፎችም ፡ ያወጣል ፡ ፍሬም ፡ ያፈራል ፡ የከበረም ፡
ዝግባ ፡ ይሆናል ፤ በበታቹም ፡ ወፎች ፡ ሁሉ ፡
ያርፋሉ ፥ በቅርንጫፎቹም ፡ ጥላ ፡ በክንፍ ፡
፳፬ የሚበርር ፡ ሁሉ ፡ ይጠጋል ። የዱር ፡ ዛፎች ፡
ሁሉ ፡ ረጅሙን ፡ ዛፍ ፡ ዝቅ ፡ ያደረግሁ ፥ አጭሩ
ንም ፡ ዛፍ ፡ ከፍ ፡ ያደረግሁ ፥ የለመለመውንም ፡
ዛፍ ፡ ያደረቅሁ ፥ የደረቀውንም ፡ ዛፍ ፡ ያለመለ
ምሁ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያው
ቃሉ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናግሬአለሁ ፡
እኔም ፡ አድርጌአለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፪ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ስለ ፡ እስራኤል ፡ ምድር ፡—
አበቶች ፡ ጨርቋ ፡ የወይን ፡ ፍሬ ፡ በሉ ፥ የልጆ
ችም ፡ ጥርሶች ፡ ጠረሱ ፡ ብላችሁ ፡ የምትመስ
፫ ሉት ፡ ምሳሌ ፡ ምንድር ፡ ነው ? እኔ ፡ ሕያው ፡
ነኝና ፡ እንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ይህን ፡ ምሳሌ ፡ በእስ
ራኤል ፡ ዘንድ ፡ አትመስሉትም ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡
፬ እግዚአብሔር ። እነሆ ፥ ነፍሳት ፡ ሁሉ ፡ የእኔ ፡
ናቸው ፤ የአባት ፡ ነፍስ ፡ የእኔ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡
ደግሞ ፡ የልጅ ፡ ነፍስ ፡ የእኔ ፡ ናት ፤ ኃጢአት ፡
የምትሠራ ፡ ነፍስ ፡ እርስዋ ፡ ትሞታለች ።
፭ ሰውም ፡ ጻድቅ ፡ ቢሆን ፡ ፍርድንና ፡ ቅን ፡ ነገ
ርን ፡ ቢያደርግ ፥ በተራራም ፡ ላይ ፡ ባይበላ ፡
፮ ዓይኖቹንም ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ቤት ፡ ጣዖታት ፡
ባያነሣ ፡ የባልንጀራውንም ፡ ሚስት ፡ ባያረክስ ፡
አደፍም ፡ ወዳለበት ፡ ሴት ፡ ባይቀርብ ፤ ሰው
፯ ንም ፡ ባያስጨንቅ ፡ ለባለ ፡ ዕዳም ፡ መያዣውን ፡
ቢመልስ ፡ ፈጽሞም ፡ ባይቀማ ፡ ከእንጀራውም ፡
ለተራበ ፡ ቢሰጥ ፡ የተራቈተውንም ፡ በልብስ ፡
ቢያለብስ ፤ በአራጣ ፡ ባያበድር ፥ ትርፎቻም ፡
፰ ባይወስድ ፥ እጁንም ፡ ከኃጢአት ፡ ቢመልስ ፥
በሰውና ፡ በሰው ፡ መካከልም ፡ የእውነትን ፡
ፍርድ ፡ ቢፈርድ ፤ በትእዛዜም ፡ ቢሄድ ፥ እው
፱ ነትንም ፡ ለማድረግ ፡ ፍርዴን ፡ ቢጠብቅ ፥ እርሱ ፡
ጻድቅ ፡ ነው ፥ ፈጽሞ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራል ፥
ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፲ እርሱም ፡ ቀማኛና ፡ ደም ፡ አፍሳሽ ፡ ልጅ ፡
ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ አንዳቸውን ፡ የሚያደርገውን ፡
ቢወልድ ፥ እርሱም ፡ ጻድቅ ፡ አባቱ ፡ የሠራ
፲፩ ውን ፡ ሁሉ ፡ ባይሠራ ፡ በተራራም ፡ ላይ ፡ ቢበላ ፡
የባልንጀራውንም ፡ ሚስት ፡ ቢያረክስ ፥ ድሀ
፲፪ ውንና ፡ ችግረኛውንም ፡ ቢያስጨንቅ ፡ ቢቀ
ማም ፡ መያዣውንም ፡ ባይመልስ ፡ ዓይኖቹንም ፡
ወደ ፡ ጣዖታት ፡ ቢያነሣ ፡ ርኩስን ፡ ነገር ፡ ቢያ
ደርግ ፥ በአራጣ ፡ ቢያበድር ፥ ትርፎቻም ፡ ቢወ
፲፫ ስድ ፥ በውኑ ፡ እርሱ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራልን ?
በሕይወት ፡ አይኖርም ፤ ይህን ፡ ርኩሰት ፡ ሁሉ ፡
አድርጎአልና ፡ ፈጽሞ ፡ ይሞታል ፤ ደሙ ፡ በላዩ ፡
ላይ ፡ ይሆናል ።

፲፬ እነሆም ፥ ልጅ ፡ ቢወልድ ፥ እርሱም ፡ አባቱ ፡
የሠራውን ፡ ኃጢአት ፡ አይቶ ፡ ቢፈራ ፡ እንዲ
ህም ፡ ባይሠራ ፥ በተራራ ፡ ላይ ፡ ባይበላ ፡ ዓይ
፲፭ ኖቹንም ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ቤት ፡ ጣዖታት ፡
ባያነሣ ፡ የባልንጀራውንም ፡ ሚስት ፡ ባያረክስ ፥
ሰውንም ፡ ባያስጨንቅ ፡ መያዣውን ፡ ባይወ
፲፮ ስድ ፡ ባይቀማም ፡ ከእንጀራውም ፡ ለተራበ ፡
ቢሰጥ ፡ ለተራቈተውም ፡ ልብስን ፡ ቢያለብስ ፥
እጁንም ፡ ድሀን ፡ ከመበደል ፡ ቢመልስ ፡ አራ
፲፯ ጣን ፡ ትርፎቻንም ፡ ባይወስድ ፡ ፍርዴንም ፡
ቢያደርግ ፡ በትእዛዜም ፡ ቢሄድ ፥ እርሱ ፡ ፈጽሞ ፡
በሕይወት ፡ ይኖራል ፡ እንጂ ፡ በአባቱ ፡ ኃጢ
አት ፡ አይሞትም ። አባቱ ፡ ግን ፡ ፈጽሞ ፡ በድ
፲፰ ሎአልና ፥ ወንድሙንም ፡ ቀምቶአልና ፥ በሕ
ዝቡም ፡ መካከል ፡ ክፉን ፡ ነገር ፡ አድርጎአልና ፡
እነሆ ፥ እርሱ ፡ በበደሉ ፡ ይሞታል ።

፲፱ እናንተ ፡ ግን ፡— ልጅ ፡ የአባቱን ፡ ኃጢአት ፡
ስለ ፡ ምን ፡ አይሸከምም ? ትላላችሁ ። ልጅ ፡
ፍርድንና ፡ ቅን ፡ ነገርን ፡ በደረገ ፡ ትእዛዜንም ፡
ሁሉ ፡ በጠበቀና ፡ በደረገ ፡ ጊዜ ፡ ፈጽሞ ፡ በሕ
ይወት ፡ ይኖራል ። ኃጢአትን ፡ የምትሠራ ፡
፳ ነፍስ ፡ እርስዋ ፡ ትሞታለች ፤ ልጅ ፡ የአባቱን ፡
ኃጢአት ፡ አይሸከምም ፥ አባትም ፡ የልጁን ፡
ኃጢአት ፡ አይሸከምም ፤ የጻድቁ ፡ ጽድቅ ፡
በራሱ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፥ የኃጢአተኛውም ፡
ኃጢአት ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ።

፳፩ ኃጢአተኛውም ፡ ከደረጋት ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፡

ቢመለስ ፡ ትእዛዜንም ፡ ሁሉ ፡ ቢጠብቅ ፡ ፍርድ
ንና ፡ ቅን ፡ ነገርንም ፡ ቢያደርግ ፡ ፈጽሞ ፡ በሕ
፳፪፤ ይወት ፡ ይኖራል ፡ እንጂ ፡ አይሞትም ። የበደ
ለው ፡ በደል ፡ ሁሉ ፡ አይታሰብበትም ፤ በሠራው ፡
፳፫፤ ጽድቅ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራል ። በውኑ ፡ ኃጢ
አተኛ ፡ ይሞት ፡ ዘንድ ፡ እፈቅዳለሁን ? ይላል ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ ከመንገዱስ ፡ ይመለስና ፡
፳፬፤ በሕይወት ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ አይደለምን ? ጻድቁ ፡
ግን ፡ ከጽድቁ ፡ ቢመለስ ፡ ኃጢአትንም ፡ ቢሠራ ፡
ኃጢአተኛውም ፡ እንደሚያደርገው ፡ ርኵሰት ፡
ሁሉ ፡ ቢያደርግ ፥ በሕይወት ፡ ይኖራልን ? የሠ
ራት ፡ ጽድቅ ፡ ሁሉ ፡ አትታሰብለትም ፤ በደረ
ገው ፡ ዓመፅና ፡ በሠራት ፡ ኃጢአት ፡ በዚያች ፡
ይሞታል ።

፳፭፤ እናንተ ፡ ግን ፡— የጌታ ፡ መንገድ ፡ የቀናች ፡
አይደለችም ፡ ትላላችሁ ። የእስራኤል ፡ ቤት ፡
ሆይ ፥ እንግዲህ ፡ ስሙ ፤ በውኑ ፡ መንገዴ ፡ የቀ
ናች ፡ አይደለችምን ? ይልቅስ ፡ የእናንተ ፡ መን
፳፮፤ ገድ ፡ ያልቀናች ፡ አይደለችምን ? ጻድቁ ፡ ከጽ
ድቁ ፡ ቢመለስ ፥ ኃጢአትንም ፡ በሠራ ፡ ጊዜ ፥
በዚያም ፡ ቢሞት ፥ እርሱ ፡ ባደረገው ፡ በደል ፡
፳፯፤ ይሞታል ። ኃጢአተኛውም ፡ ከሠራው ፡ ኃጢ
አት ፡ ቢመለስ ፡ ፍርድንና ፡ ቅን ፡ ነገርንም ፡ ቢያ
፳፰፤ ደርግ ፡ ነፍሱን ፡ ይጠብቃል ። አስቦ ፡ ከሠራው ፡
በደል ፡ ሁሉ ፡ ተመልሶአልና ፡ ፈጽሞ ፡ በሕይ
፳፱፤ ወት ፡ ይኖራል ፡ እንጂ ፡ አይሞትም ። ነገር ፡ ግን ፡
የእስራኤል ፡ ቤት ፡— የጌታ ፡ መንገድ ፡ የቀናች ፡
አይደለችም ፡ ይላል ። የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥
በውኑ ፡ መንገዴ ፡ የቀናች ፡ አይደለችምን ? ይል
ቅስ ፡ የእናንተ ፡ መንገድ ፡ ያልቀናች ፡ አይደለ
፴፤ ችምን ? የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ ስለዚህ ፡
እንደ ፡ መንገዱ ፡ በየሰዉ ፡ ሁሉ ፡ እፈርድባች
ኋለሁ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ ንስሐ ፡
ግቡ ፡ ኃጢአትም ፡ ዕንቅፋት ፡ እንዳይሆንባ
፴፩፤ ችሁ ፡ ከኃጢአታችሁ ፡ ሁሉ ፡ ተመለሱ ። የበ
ደላችሁትን ፡ በደል ፡ ሁሉ ፡ ከእናንተ ፡ ጣሉ ፡
አዲስ ፡ ልብና ፡ አዲስ ፡ መንፈስም ፡ ለእናንተ ፡
አድርጉ ፤ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ ስለ ፡ ምን ፡
፴፪፤ ትሞታላችሁ ? የምዋቹን ፡ ሞት ፡ አልፈቅድ
ምና ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ ስለዚህ ፡
ተመለሱና ፡ በሕይወት ፡ ኑሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩፤ አንተም ፡ በእስራኤል ፡ አለቆች ፡ ላይ ፡ ይህን ፡
፪፤ ሙሾ ፡ አሙሽ ፥ እንዲህም ፡ በል ፡— እናትህ ፡
ምን ፡ ነበረች ? አንበሳ ፡ ነበረች ፤ በአንበሶች ፡
መካከል ፡ ተጋደመች ፤ በደቦል ፡ አንበሶች ፡
፫፤ መካከል ፡ ግልገሎችዋን ፡ አሳደገች ። ከግልገ
ሎችዋም ፡ አንዱን ፡ አወጣች ፡ እርሱም ፡ ደቦል ፡
አንበሳ ፡ ሆነ ፤ ንጥቂያንም ፡ ተማረ ፥ ሰዎችንም ፡
፬፤ በላ ። አሕዛብም ፡ ወሬውን ፡ ሰሙ ፡ እርሱም ፡
በጕድጓዳቸው ፡ ተያዘ ፥ በሰንሰለትም ፡ አድር
፭፤ ገው ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ምድር ፡ወሰዱት ። እርስ
ዋም ፡ እንደ ፡ ደከመችና ፡ ተስፋዋ ፡ እንደ ፡
ጠፋ ፡ በየች ፡ ጊዜ ፥ ከግልገሎችዋ ፡ ሌላን ፡
፮፤ ወስዳ ፡ ደቦል ፡ አንበሳ ፡ አደረገችው ። እር
ሱም ፡ በአንበሶች ፡ መካከል ፡ ተመላለሰ ፡ ደቦል ፡
አንበሳም ፡ ሆነ ፤ ንጥቂያም ፡ ተማረ ፥ ሰዎች
፯፤ ንም ፡ በላ ። ግንቦቻቸውንም ፡ አወቀ ፥ ከተሞ
ቻቸውንም ፡ አፈረሰ ፤ ከግሣቱም ፡ ድምፅ ፡ የተ
፰፤ ነሣ ፡ ምድሪቱና ፡ ሞላዋ ፡ ጠፉች ። አሕዛብም ፡
በዙሪያው ፡ ከየአገሩ ፡ ሁሉ ፡ ተሰበሰቡበት ፤
መረባቸውንም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ዘረጉ ፡ በጕድጓ
፱፤ ዳቸውም ፡ ተያዘ ። በሰንሰለትም ፡ አድርገው ፡
በቀፎ ፡ ውስጥ ፡ አኖሩት ፡ ወደ ፡ ባቢሎንም ፡
ንጉሥ ፡ አመጡት ፤ ድምፁም ፡ በእስራኤል ፡
ተራሮች ፡ ላይ ፡ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ እንዳይሰማ ፡
ወደ ፡ አምባ ፡ አገቡት ።

፲፤ እናትህ ፡ በመልክህ ፡ በውኃ ፡ አጠገብ ፡ እንደ ፡
ተተከለች ፡ እንደ ፡ ወይን ፡ ግንድ ፡ ነበረች ፤
ከውኃም ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ የምታፈራና ፡ የም
፲፩፤ ትሰፋ ፡ ሆነች ። ለእርስዋም ፡ ብርቱዎች ፡ በት
ሮች ፡ ነበሩአት ፡ እነርሱም ፡ ለነገሥታት ፡ በት
ሮች ፡ ነበሩ ። ቁመታቸውም ፡ በዛፎች ፡ ቅርን
ጫፎች ፡ መካከል ፡ ረዘመ ፥ በጫፎቻቸውም ፡
፲፪፤ ብዛትና ፡ በርዝመታቸው ፡ ታዩ ። ነገር ፡ ግን ፡
በመዓት ፡ ተነቀለች ፡ ወደ ፡ መሬትም ፡ ተጣለች ፡
የምሥራቅም ፡ ነፋስ ፡ ፍሬዋን ፡ አደረቀ ፤ ብር
ቱዎች ፡ በትሮችዋም ፡ ተሰበሩና ፡ደረቁ ፥ እሳ
፲፫፤ ትም ፡ በላቻቸው ። አሁንም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፥
በደረቅና ፡ በተጠማች ፡ መሬት ፡ ተተከለች ።
፲፬፤ ከጫፎችዋም ፡ በትሮች ፡ እሳት ፡ ወጣች ፡ ፍሬ
ዋንም ፡ በላች ፥ የነገሥታትም ፡ በትር ፡ ይሆን ፡
ዘንድ ፡ የበረታ ፡ በትር ፡ የለባትም ። ይህ ፡ ሙሾ ፡
ነው ፥ ለልቅሶም ፡ ይሆናል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ በአ
ምስተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአሥረኛው ፡
ቀን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይጠይቁ ፡ ዘንድ ፡ ከእ
ስራኤል ፡ሽማግሌዎች ፡ አያሌ ፡ ሰዎች ፡ መጡ ፥
፪፤ በፊቴም ፡ ተቀመጡ ። የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡
፫፤ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡
ልጅ ፡ ሆይ ፥ ለእስራኤል ፡ ሽማግሌዎች ፡ ተና
ገር ፥ እንዲህም ፡ በላቸው ፡— ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እኔን ፡ ትጠይቁ ፡
ዘንድ ፡ መጥታችኋልን ? እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡
በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ አልጠየቅም ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግ
፬፤ ዚአብሔር ። ትፈርድባቸዋለህን ? የሰው ፡ ልጅ ፡
ሆይ ፥ በውኑ ፡ ትፈርድባቸዋለህን ? የአባቶቻ
፭፤ ቸውን ፡ ርኵሰት ፡ አስታውቃቸው ። እንዲህም ፡
በላቸው ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እስራኤልን ፡ በመረጥሁበት ፡ ለያዕቆ
ብም ፡ ቤት ፡ ዘር ፡ በማልሁበት ፡ ቀን ፡ በግብ
ጽም ፡ ምድር ፡ በተገለጥሁላቸውና ፡— እኔ ፡
እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ ነኝ ፡ ብዬ ፡ በማ
፮፤ ልሁላቸው ፡ ጊዜ ፥ በዚያ ፡ ቀን ፡ ከግብጽ ፡
ምድር ፡ ወዳዘጋጀሁላቸው ፥ ወተትና ፡ ማር ፡

ወደምታፈስሰው ፥ የምድርም ፡ ሁሉ ፡ ጌጥ ፡
ወደምትሆን ፡ ምድር ፡ አወጣቸው ፡ ዘንድ ፡
፯፡ ማልሁላቸው ፤ እኔም ፦ ከእናንተ ፡ እያንዳ
ንዱ ፡ የዓይኑን ፡ ርኵሰት ፡ ይጣል ፥ በግብጽም ፡
ጣዖታት ፡ አትርከሱ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አም
፰፡ ላካችሁ ፡ ነኝ ፡ አልኋቸው ። እነርሱ ፡ ግን ፡
ዐመፁብኝ ፡ ይሰሙኝም ፡ ዘንድ ፡ አልወደዱም ፥
ሁሉም ፡ እያንዳንዱ ፡ የዓይኑን ፡ ርኵሰት ፡ አል
ጣለም ፡ የግብጽንም ፡ ጣዖታት ፡ አልተወም ፤
በዚህም ፡ ጊዜ ፦ በግብጽ ፡ ምድር ፡ መካከል ፡
ቍጣዬን ፡ እፈጽምባቸው ፡ ዘንድ ፡ መዓቴን ፡
፱፡ አፈስስባቸዋለሁ ፡ አልሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ በመ
ካከላቸው ፡ ባሉ ፡ ከግብጽም ፡ ምድር ፡ አወጣ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ በፊታቸው ፡ በተገለጥሁላቸው ፡
በአሕዛብ ፡ ፊት ፡ ስሜ ፡ እንዳይረከስ ፡ ብዬ ፡
ስለ ፡ ስሜ ፡ ሠራሁ ።

፲፡ ከግብጽም ፡ ምድር ፡ አወጣኋቸው ፡ ወደ ፡
፲፩፡ ምድረ ፡ በዳም ፡ አመጣኋቸው ። ሰው ፡ ቢያደ
ርገው ፡ ኖሮ ፡ በሕይወት ፡ የሚኖርበትን ፡ ሥር
ዓቴንም ፡ ሰጠኋቸው ፥ ፍርዴንም ፡ አስታወቅ
፲፪፡ ኋቸው ። የምቀድሳቸውም ፡ እኔ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፥ በእኔና ፡
በእነርሱ ፡ መካከል ፡ ምልክት ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡
፲፫፡ ሰንበታቴን ፡ ሰጠኋቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ የእስራ
ኤል ፡ ቤት ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ዐመፁብኝ ፤ ሰው ፡
ቢያደርገው ፡ ኖሮ ፡ በሕይወት ፡ የሚኖርበት
ንም ፡ ፍርዴን ፡ ጣሱ ፥ በትእዛዜም ፡ አልሄዱም ፥
ሰንበታቴንም ፡ ፈጽመው ፡ አረከሱ ። በዚህም ፡
ጊዜ ፦ አጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ ቍጣዬን ፡ በም
፲፬፡ ድረ ፡ በዳ ፡ አፈስስባቸዋለሁ ፡ አልሁ ። ነገር ፡
ግን ፡ በፊታቸው ፡ ባወጣኋቸው ፡ በአሕዛብ ፡
ፊት ፡ ስሜ ፡ እንዳይረከስ ፡ ብዬ ፡ ስለ ፡ ስሜ ፡
፲፭፡ ሠራሁ ። ወተትና ፡ ማርም ፡ ወደምታፈስሰው ፡
የምድር ፡ ሁሉ ፡ ጌጥ ፡ ወደምትሆን ፡ ወደ ፡ ሰጠኋ
ቸው ፡ ምድር ፡ አላመጣቸውም ፡ ብዬ ፡ በምድረ ፡
፲፮፡ በዳ ፡ ማልሁባቸው ። ልባቸው ፡ ጣዖቶቻቸ
ውን ፡ ተከትሎአልና ፤ ፍርዴንም ፡ ጥሰዋልና ፥
በሥርዓቴም ፡ አልሄዱምና ፥ ሰንበታቴንም ፡
፲፯፡ አርክሰዋልና ። ነገር ፡ ግን ፡ ዓይኔ ፡ ራራችላ
ቸው ፡ እኔም ፡ አላጠፋኋቸውም ፥ በምድረ ፡
በዳም ፡ ፈጽሜ ፡ አልፈጀኋቸውም ።

፲፰፡ ለልጆቻቸውም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንዲህ ፡
አልኋቸው ፦ በአባቶቻችሁ ፡ ሥርዓት ፡ አት
ሂዱ ፡ ወጋቸውንም ፡ አትጠብቁ ፡ በጣዖቶቻቸ
፲፱፡ ውም ፡ አትርከሱ ። እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አም
ላካችሁ ፡ ነኝ ፤ በትእዛዜ ፡ ሂዱ ፡ ፍርዴንም ፡
፳፡ ጠብቁ ፡ አድርጓትም ። ሰንበታቴንም ፡ ቀድሱ ፤
እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችሁ ፡ እንደ ፡
ሆንሁ ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ በእኔና ፡ በእናንተ ፡
፳፩፡ መካከል ፡ ምልክት ፡ ይሆናሉ ። ልጆች ፡ ግን ፡
ዐመፁብኝ ፥ ሰው ፡ ቢያደርገው ፡ ኖሮ ፡ በሕይ
ወት ፡ የሚኖርባትን ፡ ፍርዴን ፡ ጠብቀው ፡
አላደረጓትም ፡ በሥርዓቴም ፡ አልሄዱም ፥
ሰንበታቴንም ፡ አረከሱ ፤ በዚህም ፡ ጊዜ ፦
መዓቴን ፡ አፈስስባቸዋለሁ ፡ ቍጣዬንም ፡ በም
፳፪፡ ድረ ፡ በዳ ፡ እፈጽምባቸዋለሁ ፡ አልሁ ። ነገር ፡
ግን ፡ እጄን ፡ መለስሁ ፥ በፊታቸውም ፡ ባወጣ
ኋቸው ፡ በአሕዛብ ፡ ፊት ፡ ስሜ ፡ እንዳይረከስ ፡
፳፫፡ ብዬ ፡ ስለ ፡ ስሜ ፡ ሠራሁ ። ደግሞም ፡ ወደ ፡
አሕዛብ ፡ እበትናቸው ፡ ዘንድ ፥ በአገሮችም ፡
እበትናቸው ፡ ዘንድ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ማልሁብ
፳፬፡ ቸው ፤ ፍርዴን ፡ አላደረጉምና ፤ ሥርዓቴንም ፡
ጥሰዋልና ፤ ሰንበታቴንም ፡ አርክሰዋልና ፤ ዓይ
ናቸውም ፡ የአባቶቻቸውን ፡ ጣዖታቶች ፡ ተከ
፳፭፡ ትለዋልና ። ደግሞም ፡ መልካም ፡ ያልሆነውን ፡
ሥርዓት ፡ በሕይወት ፡ የማይኖሩበትንም ፡
፳፮፡ ፍርድ ፡ ሰጠኋቸው ። እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡
እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እንዲያውቁ ፡ አጠፋቸው ፡ ዘንድ ፥
ማኅፀን ፡ የሚከፍተውን ፡ ሁሉ ፡ በእሳት ፡ ባሳ
ለፉ ፡ ጊዜ ፥ በመባቸው ፡ አረከስኋቸው ።

፳፯፡ ስለዚህ ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ለእስራኤል ፡
ቤት ፡ ተናገር ፡ እንዲህም ፡ በላቸው ፦ ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ በዚህም ፡ ደግሞ ፡
አባቶቻችሁ ፡ በደረጉት ፡ ዓመፅ ፡ አስቈጡኝ ።
፳፰፡ እሰጣቸውም ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ማልሁላቸው ፡
ምድር ፡ ባገባኋቸው ፡ ጊዜ ፥ ከፍ ፡ ያለውን ፡ ኮረ
ብታ ፡ ሁሉ ፡ ቅጠልማውንም ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ አዩ ፥
በዚያም ፡ መሥዋዕታቸውን ፡ ሠዉ ፡ በዚያም ፡
የሚያስቈጣኝን ፡ ቍርባናቸውን ፡ አቀረቡ ፡ በዚ
ያም ፡ ደግሞ ፡ ጣፋጩን ፡ ሽታቸውን ፡ አደረጉ ፡
በዚያም ፡ የመጠጥ ፡ ቍርባናቸውን ፡ አፈሰሱ ።
፳፱፡ እኔም ፦ እናንተ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ የምትሄዱበት ፡
ከፍታ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አልኋቸው ። እስከ ፡
ዛሬም ፡ ድረስ ፡ ስሙ ፡ ባማ ፡ ተብሎ ፡ ተጠርቶ
፴፡ አል ። ስለዚህ ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ እንዲህ ፡ በላ
ቸው ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦
እንደ ፡ አባቶቻችሁ ፡ ልማድ ፡ ትረከሳላችሁን ?
ርኵሰታቸውንም ፡ ተከትላችሁ ፡ ታመነዝራላ
፴፩፡ ችሁን ? ቍርባናችሁን ፡ ባቀረባችሁ ፡ ጊዜ ፥ ልጆ
ቻችሁንም ፡ በእሳት ፡ ባሳለፋችሁ ፡ ጊዜ ፥ እስከ ፡
ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በጣዖቶቻችሁ ፡ ትረከሳላችሁን ፡
የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ ከእናንተስ ፡ ዘንድ ፡
እጠየቃለሁን ? እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኛና ፡ ከእናንተ ፡
ዘንድ ፡ አልጠየቅም ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
፴፪፡ ሔር ፤ ለእናንተም ፦ እንደ ፡ አሕዛብና ፡ እንደ ፡
ምድር ፡ ወገኖች ፡ እንሆናለን ፥ እንጨትና ፡
ድንጋይም ፡ እናመልካለን ፡ የሚል ፡ ከልባችሁ ፡
የወጣ ፡ አሳብ ፡ አይፈጸምላችሁም ።

፴፫፡ እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ በበረታች ፡ እጅና ፡ በተ
ዘረጋች ፡ ክንድ ፡ በፈሰሰችም ፡ መዓት ፡ እነግ
ሥባችኋለሁ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።
፴፬፡ ከአሕዛብም ፡ ዘንድ ፡ አወጣችኋለሁ ፡ ከተበተና
ችሁባትም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ በበረታች ፡ እጅና ፡
በተዘረጋች ፡ ክንድ ፡ በፈሰሰችም ፡ መዓት ፡ እሰ
፴፭፡ በስባችኋለሁ ። ወደ ፡ አሕዛብም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
አመጣችኋለሁ ፡ በዚያም ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ከእና
፴፮፡ ንተ ፡ ጋር ፡ እፋረዳለሁ ። በግብጽ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
ከአባቶቻችሁ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ተፋረድሁ ፡ እን

ዲሁ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እፋረዳለሁ ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ፴፯ ከበትርም ፡ በታች ፡ አሳልፋችኋለሁ ፡ ወደ ፡ ቃል ፡ ኪዳንም ፡ እስራት ፡ አገባችኋለሁ ፤ ፴፰ ከእናንተም ፡ ዘንድ ፡ ዓመፀኞችንና ፡ የበደሉኝን ፡ እለያለሁ ፤ ከኖሩበትም ፡ ምድር ፡ አወጣቸዋለሁ ÷ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ምድር ፡ ግን ፡ አይገቡም ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ። ፴፱ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እናንተ ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ ሂዱ ÷ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ትሰሙኝ ፡ ዘንድ ፡ ባትወድዱ ፡ ሁላችሁ ፡ ጣዖቶቻችሁን ፡ እምልኩ ። ነገር ፡ ግን ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ በቍርባናችሁና ፡ በጣዖቶቻችሁ ፡ ቅዱሱን ፡ ስሜን ፡ አታረክሱም ።

፵ በቅዱሱ ፡ ተራራዬ ÷ ከፍ ፡ ባለው ፡ በእስራኤል ፡ ተራራ ፡ ላይ ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ÷ በዚያ ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ሁላቸው ፡ በምድሩ ፡ ላይ ፡ ያመልኩኛል ፤ በዚያም ፡ እቀበላቸዋለሁ ÷ በዚያም ፡ ቍርባናችሁን ፡ በኵራታችሁንም ፡ የቀደሳችሁትንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እፈልጋለሁ ። ፵፩ ከአሕዛብም ፡ ዘንድ ፡ በወጣችሁ ፡ ጊዜ ፡ ከተበተናችሁባትም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ በሰበሰብኋችሁ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ጣፋጭ ፡ ሽታ ፡ እቀበላችኋለሁ ÷ በአሕዛብም ፡ ፊት ፡ እቀደስባችኋለሁ ። ፵፪ ለአባቶቻችሁም ፡ እሰጣት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ማልሁላቸው ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ አገር ፡ በገባኋችሁ ፡ ጊዜ ÷ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ። ፵፫ በዚያም ፡ የረከሳችሁባትን ፡ መንገዳችሁንና ፡ ሥራችሁን ፡ ሁሉ ፡ ታስባላችሁ ፤ ስለ ፡ ሠራችሁትም ፡ ክፋታችሁ ፡ ሁሉ ፡ ራሳችሁን ፡ ትጸየፋላችሁ ። ፵፬ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ እንደ ፡ ክፉ ፡ መንገዳችሁና ፡ እንደ ፡ ርኩስ ፡ ሥራችሁ ፡ ሳይሆን ፡ ስለ ፡ ስሜ ፡ ስል ፡ በሠራሁላችሁ ፡ ጊዜ ÷ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፵፭ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ፵፮ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ፊትህን ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ አቅና ፡ ወደ ፡ ደቡብም ፡ ተናገር ፡ በደቡብም ፡ ባለው ፡ ዱር ፡ ላይ ፡ ትንቢት ፡ ተናገር ፤ ፵፯ ለደቡብም ፡ ዱር ፡— የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስማ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ በአንተ ፡ ውስጥ ፡ እሳት ፡ አነድዳለሁ ፤ በውስጥህም ፡ ያለውን ፡ የለመለመውንና ፡ የደረቀውን ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ይበላል ፤ የሚቃጠል ፡ ነበልባል ፡ አይጠፋም ፤ ከደቡብም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሰሜን ፡ ድረስ ፡ ፊት ፡ ሁሉ ፡ ይቃጠልበታል ። ፵፰ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳነደድሁት ፡ ሥጋ ፡ ለባሽ ፡ ሁሉ ፡ ያያል ÷ እርሱም ፡ አይጠፋም ፡ በለው ። ፵፱ እኔም ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ÷ ወዮ ! እነርሱ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡— ይህ ፡ ምሳሌን ፡ የሚመስል ፡ አይደለምን ? ብለዋል ፡ አልሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ፪ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ፊትህን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ አቅና ፡ ወደ ፡ መቅደሶችም ፡ ተናገር ፡ በእስራኤልም ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ ትንቢት ፡ ተናገር ። ፫ ለእስራኤልም ፡ ምድር ፡ እንዲህ ፡ በል ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ በአንተ ፡ ላይ ፡ ነኝ ÷ ሰይፌንም ፡ ከሰገባው ፡ እመዝዘዋለሁ ÷ ጻድቁንና ፡ ክፉውንም ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ አጠፋለሁ ። ፬ እኔም ፡ ጻድቁንና ፡ ክፉውን ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ ስለማጠፋ ÷ ስለዚህ ፡ ሰይፌ ፡ ከደቡብ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሰሜን ፡ ድረስ ፡ ባለ ፡ በሥጋ ፡ ለባሽ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከሰገባው ፡ ይመዘዛል ። ፭ ሥጋ ፡ ለባሹም ፡ ሁሉ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰይፌን ፡ ከሰገባው ፡ እንደ ፡ መዘዝሁ ፡ ያውቃል ÷ እርሱም ፡ ደግሞ ፡ አይመለስም ። ፮ ስለዚህም ÷ አንተ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ አልቅስ ፤ ወገብህን ፡ በማጕበጥ ፡ በፊታቸው ፡ ምርር ፡ ብለህ ፡ አልቅስ ። ፯ እነርሱም ፡— ስለ ፡ ምን ፡ ታለቅሳለህ ? ቢሉህ ÷ አንተ ፡ እንዲህ ፡ በላቸው ፡— ወሬ ፡ ስለሚመጣ ፡ ነው ፤ ልብም ፡ ሁሉ ፡ ይቀልጣል ÷ እጆችም ፡ ሁሉ ፡ ይዝላሉ ÷ ነፍስም ፡ ሁሉ ፡ ትደክማለች ÷ ጕልበትም ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ ይፈስሳል ፤ እነሆ ÷ ይመጣል ፡ ይፈጸምማል ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፰ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ፱ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፡— እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡ ብለህ ፡ ትንቢት ፡ ተናገር ፤ ሰይፍ ፡ ሰይፍ ፡ የተሳለ ፡ የተሰነገለም ፡ ነው ፡ በል ። ፲ ይገድል ፡ ዘንድ ፡ ተስሎአል ፡ ያብረቀርቅም ፡ ዘንድ ፡ ተሰንግሎአል ፤ እኛስ ፡ ደስ ፡ ይለናልን ? የልጄን ፡ በትር ፡ እንደ ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ንቆታል ። ፲፩ በእጁም ፡ እንዲያዝ ፡ ለመሰንገል ፡ ተሰጠ ፤ ሰይፍ ፡ በገዳይ ፡ እጅ ፡ እንዲሰጥ ፡ ተሳለና ፡ ተሰነገለ ። ፲፪ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ በሕዝቤ ፡ ላይ ፡ ነውና ÷ በእስራኤል ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነውና ፡ ጩኽ ፡ ዋይም ፡ በል ፤ እነርሱ ፡ ከሕዝቤ ፡ ጋር ፡ ለሰይፍ ፡ ተሰጥተዋል ፤ ስለዚህ ፡ ጭንህን ፡ ጽፋ ። ፲፫ ፈተና ፡ ደርሶአል ፤ የተናቀ ፡ በትርስ ፡ ደግሞ ፡ ባይኖር ፡ ምንድር ፡ ነው ? ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ፲፬ ስለዚህ ÷ አንተ ፡ የሰው ፡ ልጅ ÷ ትንቢት ፡ ተናገር ÷ እጅህን ፡ አጨብጭብ ፤ የተገደሉ ፡ ሰዎች ፡ ሰይፍ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ይደጋግም ፤ የሚከብባቸው ፡ የተገደለ ፡ የታላቅ ፡ ሰው ፡ ሰይፍ ፡ ነው ። ፲፭ ልባቸው ፡ እንዲቀልጥ ፡ መሰናክላቸውም ፡ እንዲበዛ ፡ የሚገድለውን ፡ ሰይፍ ፡ በበሮቻቸው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አድርጌአለሁ ፤ ወዮ ! ያብረቀርቅ ፡ ዘንድ ፡ ተሰንግሎአል ፡ ይገድልም ፡ ዘንድ ፡ ተስሎአል ። ፲፮ ተዘጋጅተህ ፡ ፊትህ ፡ ወደ ፡ ወደደው ፡ ወደ ፡ ቀኝ ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ ግራ ፡ ሂድ ። ፲፯ እኔ ፡ ደግሞ ፡

በእጄ ፡ አጨበጭባለሁ ፡ መዓቴንም ፡ እጨርሰ
ለሁ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናግሬአለሁ ።
፲፰ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፲፱ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— አንተም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡
ሆይ ÷ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ሰይፍ ፡ ይመጣ ፡
ዘንድ ፡ ሁለት ፡ መንገዶችን ፡ አድርግ ፤ ሁለቱም ፡
ከአንዲት ፡ ምድር ፡ ይውጡ ፤ ምልክትም ፡ አድ
ርግ ÷ በከተማይቱ ፡ መንገድ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ አድ
፳ ርገው ። ሰይፍ ፡ ወደ ፡ አሞን ፡ ልጆች ፡ አገር ፡
ወደ ፡ ረባት ፡ ወደ ፡ ይሁዳም ፡ ወደ ፡ ተመሸገች ፡
ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ መንገድን ፡
፳፩ አድርግ ። የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ምዋርቱን ፡ ያም
ዋርት ፡ ዘንድ ፡ በመንታ ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ በሁ
ለቱ ፡ መንገዶች ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፤ ፍላጻ
ችን ፡ ወዘወዘ ÷ ከተራፊምም ፡ ጠየቀ ÷ ጉበትም ፡
፳፪ ተመለከተ ። የቅጥሩን ፡ ማፍረሻ ፡ ያደርግ ፡
ዘንድ ÷ አፍንም ፡ በጩኸት ፡ ይከፍት ፡ ዘንድ ÷
በውካታም ፡ ድምፅን ፡ ከፍ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ÷ የቅ
ጥሩን ፡ ማፍረሻ ፡ በበሮች ፡ ላይ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ÷
አፈርን ፡ ይደለድል ፡ ዘንድ ÷ ምሽግም ፡ ይሠራ ፡
ዘንድ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ዕጣ ፡ በቀኝ ፡ እጁ ፡ ውስጥ ፡
፳፫ ነበረ ። መሐላውንም ፡ በማሉ ፡ በዓይናቸው ፡
ዘንድ ፡ የሐሰት ፡ ምዋርት ፡ ይመስላል ÷ ነገር ፡
ግን ፡ እነርሱ ፡ ይያዙ ፡ ዘንድ ፡ እርሱ ፡ ኃጢአ
ትን ፡ ያሳስባል ።
፳፬ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— ኃጢአታችሁን ፡ ስለ ፡ አሰባችሁ ፡
መተላለፋችሁም ፡ ስለ ፡ ተገለጠ ፡ ኃጢአታች
ሁም ፡ በሥራችሁ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ታየ ፡ እናንተም ፡
፳፭ ስለ ፡ ታሰባችሁ ÷ በእጅ ፡ ትያዛላችሁ ። አን
ተም ፡ ቀንህ ፡ የደረሰብህ ÷ የኃጢአትህ ፡ ቀጠሮ ፡
ጊዜ ፡ የደረሰብህ ÷ ርኩስ ፡ ኃጢአተኛ ፡ የእስ
፳፮ ራኤል ፡ አለቃ ፡ ሆይ ÷ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— መጠምጠሚያውን ፡ አው
ልቅ ÷ ዘውዱንም ፡ አርቅ ፤ ይህ ፡ እንዲህ ፡ አይ
ሆንም ፤ የተዋረደውን ፡ ከፍ ፡ አድርግ ÷ ከፍ ፡
፳፯ ያለውንም ፡ አዋርድ ። ባድማ ÷ ባድማ ÷ ባድማ ፡
አደርጋታለሁ ፤ ፍርድ ፡ ያለው ፡ እስኪመጣ ፡
ድረስ ፡ ይህች ፡ ደግሞ ፡ አትሆንም ÷ ለእርሱም ፡
እሰጣታለሁ ።
፳፰ ፳፱ አንተም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፡— ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ስለ ፡ አሞን ፡ ልጆችና ፡ ስለ ፡ ስድ
ባቸው ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡ ብለህ ፡ ትንቢት ፡
ተናገር ፤ ቀናቸው ፡ በደረሰ ÷ የኃጢአታቸው ፡
ቀጠሮ ፡ ጊዜ ፡ በደረሰ ÷ በተገደሉት ፡ ኃጢ
አተኞች ፡ አንገት ፡ ላይ ፡ ያኖሩህ ፡ ዘንድ ፡
ከንቱን ፡ ራእይ ፡ ነገር ፡ሲያዩልህ ፡ በሐሰትም ፡
ምዋርት ፡ ሲናገሩልህ ፡— ሰይፍ ÷ ሰይፍ ፡ ተመ
ዝዞአል ÷ ይገድልም ፡ ዘንድ ፡ ያብረቀርቅም ፡
፴ ዘንድ ፡ ተሰንግሎአል ፡ በል ። ወደ ፡ ሰገባውም ፡
መልሰው ። በተፈጠርህበት ፡ ስፍራ ፡ በተወለ
፴፩ ድህባትም ፡ ምድር ፡ እፈርድብሃለሁ ። ቍጣ
ዬንም ፡ አፈስስብሃለሁ ÷ በመዓቴም ፡ እሳት ፡
እናፋብሃለሁ ÷ ማጥፋትንም ፡ ለሚያውቁ ፡ ለጨ
ካኞች ፡ ሰዎች ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጥሃለሁ ።
፴፪ ለእሳት ፡ ማገዶ ፡ ትሆናለህ ÷ ደምህም ፡ በምድር ፡
መካከል ፡ ይሆናል ÷ ደግሞም ፡ አትታሰብም ፤
እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናግሬአለሁና ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፪ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— አንተም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡
ሆይ ÷ ትፈርዳለህን ? ደም ፡ በምታፈስስ ፡
ከተማ ፡ ላይ ፡ ትፈርዳለህን ? ርኵሰትዋን ፡ ሁሉ ፡
፫ አስታውቃት ። እንዲህም ፡ በል ፡— ጌታ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ጊዜሽ ፡ እንዲደ
ርስ ፡ በመካከልሽ ፡ ደምን ፡ የምታፈስሺ ፡ እን
ድትረክሺም ፡ በራስሽ ፡ ላይ ፡ ጣዖታትን ፡ የም
፬ ታደርጊ ፡ ከተማ ፡ ሆይ ! ባፈሰስሽው ፡ ደም ፡
በድለሻል ፡ ባደረግሽውም ፡ ጣዖታት ፡ ረክሰሻል ፤
ቀንሽን ፡ አቀረብሽ ፡ ዘመንሽንም ፡ አሳጠርሽ ፤
ስለዚህ ፡ ለአሕዛብ ፡ መሰደቢያ ፡ ለአገሮችም ፡
፭ ሁሉ ፡ መሳለቂያ ፡ አደረግሁሽ ። አንቺ ፡ ስምሽ ፡
የረከሰ ፡ ሽብርም ፡ የሞላብሽ ፡ ሆይ ÷ ወደ ፡
አንቺ ፡ የቀረቡና ፡ ከአንቺ ፡ የራቁ ፡ ይሳለቁብ
ሻል ።
፮ እነሆ ÷ የእስራኤል ፡ አለቆች ፡ እያንዳንዱ ፡
እንደ ፡ ችሎቱ ፡ ደም ፡ ያፈስሱ ፡ ዘንድ ፡ በአ
፯ ንቺ ፡ ውስጥ ፡ ነበሩ ። በአንቺ ፡ ውስጥ ፡ አባት
ንና ፡ እናትን ፡ አቃለሉ ፤ በመካከልሽ ፡ በመጻ
ተኛው ፡ ላይ ፡ በደልን ፡ አደረጉ ፤ በአንቺ ፡
ውስጥ ፡ ድሀ ፡ አደጉንና ፡ መበለቲቱን ፡ አስጨ
፰ ነቁ ። ቅድሳቴንም ፡ ናቅሽ ፡ ሰንበታቴንም ፡
፱ አረከስሽ ። ደምን ፡ ያፈስሱ ፡ ዘንድ ፡ ቀማኞች ፡
ሰዎች ፡ በአንቺ ፡ ውስጥ ፡ ነበሩ ፤ በአንቺ ፡
ውስጥ ፡ በተራሮች ፡ ላይ ፡ በሉ ፤ በመካከልሽ ፡
፲ ሴሰኝነትን ፡ አደረጉ ። በአንቺ ፡ ውስጥ ፡ የአባ
ቶቻቸውን ፡ ኀፍረተ ፡ ሥጋ ፡ ገለጡ ፤ በአን
ቺም ፡ ውስጥ ፡ አደፍ ፡ ያለባትን ፡ አዋረዱ ።
፲፩ ሰውም ፡ በባልንጀራው ፡ሚስት ፡ ርኵሰትን ፡
አደረገ ÷ አባትም ፡ የልጁን ፡ ሚስት ፡ አረከሰ ÷
በአንቺም ፡ ዘንድ ፡ ወንድም ፡ የአባቱን ፡ ልጅ ፡
፲፪ እኅቱን ፡ አሳፈረ ። በአንቺ ፡ ውስጥ ፡ ደምን ፡ ያፈ
ስሱ ፡ ዘንድ ፡ ጉቦን ፡ ተቀበሉ ፤ አንቺም ፡ አራ
ጣና ፡ ትርፍ ፡ ወስደሻል ÷ ከባልንጀሮችሽም ፡
በቅሚያ ፡ የስስትን ፡ ትርፍ ፡ አገኘሽ ÷ እኔ
ንም ፡ ረሳሽኝ ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።
፲፫ ስለዚህ ÷ እነሆ ÷ አንቺ ፡ ባደረግሽው ፡ ስስት ፡
በመካከልሽም ፡ በነበረው ፡ ደም ፡ ላይ ፡ እጄን ፡
፲፬ አጨበጨብሁ ። በውኑ ፡ እኔ ፡ በማደርግብሽ ፡
ወራት ፡ ልብሽ ፡ ይታገሣልን ? ወይስ ፡ እጅሽ ፡
ትጸናለችን ? እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናግሬአ
፲፭ ለሁ ፡ አደርገውማለሁ ። ወደ ፡ አሕዛብም ፡ እበ
ትንሻለሁ ፡ ወደ ፡ አገሮችም ፡ እዘራሻለሁ ÷
ርኵሰትሽንም ፡ ከአንቺ ፡ ዘንድ ፡ አጠፋለሁ ።
፲፮ በአሕዛብም ፡ ፊት ፡ አንቺ ፡ ትረክሻለሽ ፡ እኔም ፡
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቂአለሽ ።
፲፯ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን

፲፰ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ለእኔ ፡ እንደ ፡ አተላ ፡ ሆኑብኝ ፤ እነርሱ ፡ ሁሉ ፡ በከውር ፡ ውስጥ ፡ መዳብና ፡ ቈርቈሮ ፡ ብረትና ፡ እርሳስ ፡ ናቸው ፤ የብር ፡
፲፱ አተላ ፡ ናቸው ። ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ሁላችሁ ፡ አተላ ፡ ሆናችኋልና ፡ ስለዚህ ፥ እነሆ ፥ በኢየሩሳሌም ፡ ውስጥ ፡
፳ እሰበስባችኋለሁ ። እንዲያቀልጡት ፡ እሳት ፡ ያናፉበት ፡ ዘንድ ፡ ብርንና ፡ መዳብን ፡ ብረትንና ፡ እርሳስን ፡ ቈርቈሮንም ፡ በከውር ፡ እንደሚሰበስቡ ፥ እንዲሁ ፡ በቍጣዬና ፡ በመዓቴ ፡ እሰበስባችኋለሁ ፥ በዚያም ፡ ውስጥ ፡ እጨምራችኋ
፳፩ ለሁ ፡ አቀልጣችሁማለሁ ። እሰበስባችሁማለሁ ፡ የመዓቴንም ፡ እሳት ፡ አናፋባችኋለሁ ፡
፳፪ በውስጡም ፡ ትቀልጣላችሁ ። ብርም ፡ በከውር ፡ ውስጥ ፡ እንደሚቀልጥ ፥ እንዲሁ ፡ በውስጡዋ ፡ ትቀልጣላችሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ መዓቴን ፡ እንዳፈሰስሁባችሁ ፡ ታውቃላችሁ ።

፳፫ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፳፬ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፡— አንቺ ፡ ያልነጻሽ ፡ በቍጣም ፡ ቀን ፡ ያልዘነበ
፳፭ ብሽ ፡ ምድር ፡ ነሽ ፡ በላት ። በውስጥዋ ፡ ያሉ ፡ ነቢያት ፡ እንደሚጮኽና ፡ እንደሚናጠቅ ፡ አንበሳ ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡ ተማማሉ ፤ ነፍሶችን ፡ በልተዋል ፥ ብልጥግናና ፡ ሀብትን ፡ ወስደዋል ፥
፳፮ በውስጥዋም ፡ መበለቶችን ፡ አብዝተዋል ። ካህናቶችዋም ፡ ሕጌን ፡ በድለዋል ፡ ቅድሳቴንም ፡ አርክሰዋል ፤ ቅዱስ ፡ በሆነና ፡ ቅዱስ ፡ ባልሆነ ፡ መካከልም ፡ አልለዩም ፥ በንጹሕና ፡ በርኩስ ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ ልዩነት ፡ አላስታወቁም ፤ ዓይናቸውንም ፡ ከሰንበታቴ ፡ ሰወሩ ፡ እኔም ፡ በመካከላ
፳፯ ቸው ፡ ረከስሁ ። በውስጥዋ ፡ ያሉ ፡ አለቆችዋ ፡ የስስትን ፡ ትርፍ ፡ ለማግኘት ፡ ሲሉ ፡ ደምን ፡ ያፈስሱ ፡ ዘንድ ፡ ነፍሶችንም ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡
፳፰ እንደሚናጠቁ ፡ ተኵላዎች ፡ ናቸው ። እግዚአብሔርም ፡ ሳይናገር ፡ ነቢያቶችዋ ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡ እያሉ ፡ ከንቱን ፡ ራእይ ፡ በማየት ፡ የሐሰትንም ፡ ምዋርት ፡ ለእነርሱ ፡ በማምዋረት ፡ ያለ ፡ ገለባ ፡ በጭቃ ፡ ይመር
፳፱ ጓቸዋል ። የምድርን ፡ ሕዝብ ፡ ግፍ ፡ አደረጉ ፡ ቅሚያም ፡ ሠሩ ፤ ድሆችንና ፡ ችግረኞችን ፡
፴ አስጨነቁ ፥ መጻተኛውንም ፡ በደሉ ። ቅጥርን ፡ የሚጠግንን ፥ ምድሪቱንም ፡ እንዳላጠፋት ፡ በፈረሰበት ፡ በኩል ፡ በፊቴ ፡ የሚቆምላትን ፡ ሰው ፡ በመካከላቸው ፡ ፈለግሁ ፥ ነገር ፡ ግን ፡
፴፩ አላገኘሁም ። ስለዚህ ፡ ቍጣዬን ፡ አፈሰስሁባቸው ፥ በመዓቴም ፡ እሳት ፡ አጠፋኋቸው ፤ መንገዳቸውንም ፡ በራሳቸው ፡ ላይ ፡ መለስሁ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡
፪ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ የአንዲት ፡ እናት ፡ ልጆች ፡ የሆኑ ፡ ሁለት ፡ ሴቶች ፡ ነበሩ ።
፫ በግብጽም ፡ አመነዘሩ ፥ በኰረዳነታቸው ፡ አመነዘሩ ፤ በዚያ ፡ ጡቶቻቸው ፡ ምዋሸሹ ፡ በዚያም ፡ የድንግልናቸውን ፡ ጡቶች ፡ ዳበሱ ።
፬ ስማቸውም ፡ የታላቂቱ ፡ አሖላ ፡ የእኅትዋም ፡ አሖሊባ ፡ ነበረ ፥ ለእኔም ፡ ሆኑ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆችንም ፡ ወለዱ ። ስማቸውም ፡ አሖላ ፡ ሰማርያ ፡ ናት ፤ አሖሊባ ፡ ደግሞ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ናት ።

፭ አሖላም ፡ ገለሞተችብኝ ፥ ውሽሞችዋንም ፡ ጎረቤቶችዋን ፡ አሦራውያንን ፡ በፍቅር ፡ ተከተ
፮ ለቻቸው ። እነርሱም ፡ሰማያዊ ፡ ሐር ፡ የለበሱ ፡ አለቆችና ፡ ሹማምቶች ፥ መልከ ፡ መልካሞች ፡ ጕበዛዝት ፥ በፈረስ ፡ ላይ ፡ የሚቀመጡ ፡ ፈረ
፯ ሰኞች ፡ ነበሩ ። ግልሙትናዋንም ፡ ከተመረጡ ፡ ከአሦር ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ አደረገች ፥ በፍቅር ፡ በተከተለቻቸውም ፡ ጣዖቶቻቸው ፡ ሁሉ ፡
፰ ረከሰች ። በግብጽም ፡ የነበረውን ፡ ግልሙትናዋን ፡ አልተወችም ፤ በዚያ ፡ በኰረዳነትዋ ፡ ጊዜ ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ ተኝተው ፡ ነበር ፥ የድንግልናዋንም ፡ ጡቶች ፡ ዳብሰው ፡ ነበር ፥ ግልሙትናቸውንም ፡ አፍስሰውባት ፡ ነበር ።
፱ ስለዚህ ፡ በፍቅር ፡ በተከተለቻቸው ፡ በውሽሞችዋ ፡ በአሦራውያን ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ ሰጠ
፲ ኋት ። እነርሱም ፡ ኀፍረተ ፡ ሥጋዋን ፡ ገለጡ ፤ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆችዋንም ፡ ማርከው ፡ ወሰዱ ፥ እርስዋንም ፡ በሰይፍ ፡ ገደሉ ፤ ፍርድንም ፡ ስላደረጉባት ፡ በሴቶች ፡ መካከል ፡ መተረቻ ፡ ሆነች ።

፲፩ እኅትዋም ፡ አሖሊባ ፡ ይህን ፡ አየች ፤ ሆኖም ፡ ከእርስዋ ፡ ይልቅ ፡ በፍቅር ፡ በመከተልዋ ፡ ረከሰች ፥ ግልሙትናዋም ፡ ከእኅትዋ ፡ ግልሙ
፲፪ ትና ፡ ይልቅ ፡ በዛ ። አለቆችንና ፡ ሹማምቶችን ፡ ጎረቤቶችዋን ፡ ጌጠኛ ፡ ልብስ ፡ የለበሱትን ፡ በፈረሶች ፡ ላይ ፡ የሚቀመጡትን ፡ ፈረሰኞች ፥ ሁሉም ፡ መልከ ፡ መልካሞችን ፡ ጕበዛዝት ፡
፲፫ አሦራውያንን ፡ በፍቅር ፡ ተከተለቻቸው ። የረከሰችም ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ አየሁ ፥ ሁለቱም ፡
፲፬ አንድ ፡ መንገድ ፡ ሄደዋል ። ግልሙትናዋንም ፡ አበዛች ፤ በቀይ ፡ ቀለምም ፡ የተሳለችውን ፡ የከለዳውያንን ፡ ስዕል ፥ በናስ ፡ ላይ ፡ የተሳሉትን ፡
፲፭ ሰዎች ፡ አየች ። በወገባቸው ፡ ዝናር ፡ የታጠቁ ፡ ራሳቸውንም ፡ በቀለማዊ ፡ መጠምጠሚያ ፡ የጠመጠሙ ፡ ነበሩ ፤ ሁሉም ፡ ከተወለዱባት ፡ አገር ፡ የሆኑትን ፡ የከለዳውያንን ፡ ልጆች ፡ መስለው ፡
፲፮ መሳፍንትን ፡ ይመስሉ ፡ ነበር ። ባየቻቸውም ፡ ጊዜ ፡ በፍቅር ፡ ተከተለቻቸው ፥ ወደ ፡ ከላውዴዎን ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ መልእክተኞችን ፡
፲፯ ላከች ። የባቢሎንም ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ፍቅር ፡ ወዳለበት ፡ መኝታ ፡ መጡ ፡ በግልሙትናቸውም ፡ አረከሱአት ፤ እርስዋም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ረከሰች ፡ ነፍስዋም ፡ ከእነርሱ ፡ ተለየች ።
፲፰ ግልሙትናዋንም ፡ ገለጠች ፡ ኀፍረተ ፡ ሥጋዋንም ፡ አሳየች ፤ ነፍሴም ፡ ከእኅትዋ ፡ እንደ ፡ ተለየች ፡ እንዲሁ ፡ ነፍሴ ፡ ከእርስዋ ፡ ተለየች ።

፲፱ ነገር፡ግን፡በግብጽ፡ምድር፡የገለሞተችበትን፡የኰረዳነትዋን ፡ ዘመን ፡ አስባ ፡ ግልሙትናዋን፡አበዛች ። ፳ ሥጋቸውም፡እንደ፡አህዮች፡ሥጋ፡ዘራቸውም፡እንደ፡ፈረሶች፡ዘር፡የሆነውን፡እነዚያን፡ምልምሎች፡በፍቅር፡ተከተለቻቸው ። ፳፩ ስለ፡ኰረዳነትሽ፡ምክንያት፡ግብጻውያን፡ጡቶችሽን፡በዳበሱ፡ጊዜ፡የኰረዳነትሽን፡ሴሰኝነት፡አሰብሽ ።

፳፪ ስለዚህ ÷ አሖሊባ ፡ ሆይ ÷ ጌታ ፡ እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል ፡— ነፍስሽ፡ከእነርሱ፡የተለየች፡ውሽሞችሽን፡አስነሣብሻለሁ÷በዙርያሽም ፡ በአንቺ ፡ ላይ ፡ አመጣቸዋለሁ ። ፳፫ እነርሱም፡የባቢሎን፡ሰዎች፡ከለዳውያንም፡ሁሉ÷ፋቁድ÷ሱሔ÷ቆዓ÷ከእነርሱም፡ጋር፡አሦራውያን፡ሁሉ÷መልከ፡መልካሞች፡ጉበዛዝት÷አለቆችና፡ሹማምቶች፡ሁሉ÷መሳፍንቶችና፡አማካሪዎች፡ሁሉ÷በፈረስ፡ላይ፡የተቀመጡ፡ናቸው ። ፳፬ በመሣሪያና፡በሰረገላ፡በመንኰራኩርም፡በአሕዛብም፡ጉባኤ፡ይመጡብሻል ፤ ጋሻና፡አላባሽ፡ጋሻ፡ራስ፡ቍርም፡ይዘው ፡ በዙሪያሽ ፡ ይዘጋጁብሻል ፤ ፍርድንም፡እሰጣቸዋለሁ÷እንደ፡ፍርዳቸውም፡ይፈርዱብሻል ። ፳፭ ቅንዓቴንም፡በአንቺ፡ላይ፡አደርጋለሁ፡በመዓትም፡ያደርጉብሻል ፤ አፍንጫሽንና፡ጆሮሽንም፡ከአንቺ፡ይቈርጣሉ÷ከአንቺም ፡ የቀረ ፡ በሰይፍ ፡ ይወድቃል ፤ ወንዶችና፡ሴቶች፡ልጆችሽንም፡ማርከው፡ይወስዳሉ÷ከአንቺም፡የቀረውን፡እሳት፡ትበላቸዋለች ። ፳፮ ልብስሽንም፡ይገፍፉሻል፡የክብርሽንም፡ጌጥ፡ይወስዳሉ ። ፳፯ ሴሰኝነትሽንም÷ከግብጽ፡ምድር፡ያወጣሽውን፡ግልሙትናሽንም፡ከአንቺ፡አስቀራለሁ ፤ ዓይንሽንም፡ወደ፡እነርሱ፡አታነሺም፡ግብጽንም፡ከዚያ፡ወዲያ፡አታስቢም ። ፳፰ ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላልና ፡— እነሆ ÷ በጠላሻቸው ፡ እጅ ÷ ነፍስሽ፡በተለየቻቸው፡እጅ፡አሳልፌ፡እሰጥሻለሁ ፤ ፳፱ እነርሱም ፡ በጥል ፡ ያደርጉብሻል ÷ የደከምሽበትንም፡ሁሉ፡ይወስዳሉ÷ዕራቁትሽንና፡ዕርቃንሽን፡አድርገውም፡ይተዉሻል ፤ የግልሙትናሽም፡ነውር÷ሴሰኝነትሽና፡ግልሙትናሽም፡ሁሉ፡ይገለጣል ። ፴ ከአሕዛብ፡ጋር፡ስላመነዘርሽ፡በጣዖቶቻቸውም፡ስለ፡ረከስሽ፡ይህን ፡ ያደርጉብሻል ። ፴፩ በእኅትሽ ፡ መንገድ ፡ ሄደሻል ፤ ስለዚህ፡ጽዋዋን፡በእጅሽ፡እሰጥሻለሁ ። ፴፪ ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል ፡— የጠለቀውንና፡የሰፋውን፡ብዙም፡የሚይዘውን፡የእኅትሽን፡ጽዋ፡ትጠጪአለሽ ፤ መሳቂያና፡መሳለቂያም፡ትሆኛለሽ ። ፴፫ በእኅትሽ፡በሰማርያ፡ጽዋ÷በድንጋጤና፡በጥፋት፡ጽዋ÷በስካርና፡በውርደት፡ትሞልያለሽ ። ፴፬ ትጠጪዋለሽ፡ትጨልጪውማለሽ፡ገሉንም፡ታኝኪዋለሽ፡ጡትሽንም፡ትሸነትሪዋለሽ ፤ እኔ፡ተናግሬአለሁና÷ይላል፡እግዚአብሔር ። ፴፭ ስለዚህ፡ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል ፡— ዘንግተሽኛልና ÷ ወደ ፡ ኋላሽም ፡ ጥለሽኛልና ፡ አንቺ፡ደግሞ፡ሴሰኝነትሽንና፡ግልሙትናሽን፡ተሸከሚ ።

፴፮ እግዚአብሔርም፡እንዲህ፡አለኝ ፡— የሰው፡ልጅ፡ሆይ÷በአሖላና፡በአሖሊባ፡ትፈርዳለህን? ኀጢአታቸውንም፡ታስታውቃቸዋለህን? ፴፯ አመንዝረዋልና÷ደምም፡በእጃቸው፡አለና÷ከጣዖቶቻቸውም፡ጋር፡አመንዝረዋልና÷ለእኔም፡የወለዱአቸውን፡ልጆቻቸውን፡መብል፡እንዲሆኑላቸው፡በእሳት፡አሳልፈዋቸዋልና ። ፴፰ ይህን፡ደግሞ፡አድርገውብኛል ፤ በዚያ፡ቀን፡መቅደሴን፡አርክሰዋል፡ሰንበታቴንም፡ሽረዋል ። ፴፱ ልጆቻቸውንም፡ለጣዖቶቻቸው፡በሠዉ፡ጊዜ÷በዚያው፡ቀን፡ያረክሱት፡ዘንድ፡ወደ፡መቅደሴ፡ገቡ ፤ እነሆም÷በቤቴ፡ውስጥ፡እንደዚህ፡አደረጉ ። ፵ ደግሞ፡መልእክተኛ፡ወደ፡ተላከባቸው፡ከሩቅም፡ወደሚመጡ፡ሰዎች፡ልካችኋል ፤ እነሆም፡መጡ÷አንቺም፡ታጠብሽላቸው፡ዓይኖችሽንም፡ተኳልሽ፡ጌጥም፡አጌጥሽ ፤ ፵፩ በክብር፡አልጋ፡ላይ፡ተቀመጥሽ÷በፊት፡ለፊትዋም፡ማዕድ፡ተዘጋጅታ፡ነበር÷ዕጣኔንና፡ዘይቴንም፡አኖርሽበት ። ፵፪ የደስተኞችም፡ድምፅ፡በእርስዋ፡ዘንድ፡ነበረ ፤ ከብዙም፡ሰዎች፡ጉባኤ፡ጋር፡ሰካራሞቹ፡ከምድረ፡በዳ፡መጡ ፤ በእጃቸው፡አንበር፡በራሳቸውም፡የተዋበ፡አክሊል፡አደረጉ ። ፵፫ እኔም፡በምንዝር፡ላረጀችው ፡— አሁን፡ከእርስዋ፡ጋር፡ያመነዝራሉ፡እርስዋም፡ከእነርሱ፡ጋር፡ታመነዝራለች፡አልሁ ። ፵፬ ወደ፡ጋለሞታም፡እንደሚገቡ፡ወደ፡እርስዋ፡ገቡ ፤ እንዲሁ፡ይሰስኑ፡ዘንድ፡ወደ፡አሖላና፡ወደ፡አሖሊባ፡ገቡ ። ፵፭ ሴቶቹ፡አመንዝሮች፡ናቸውና÷በእጃቸውም፡ደም፡አለና፡ጻድቃን፡ሰዎች፡በአመንዝሮቹና፡በደም፡አፍሳሾቹ፡ሴቶች፡ላይ፡በሚፈረደው፡ፍርድ፡ይፈርዱባቸዋል ።

፵፮ ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል ፡— ጉባኤን፡አመጣባቸዋለሁ÷ለመበተንና፡ለመበዝበዝም፡አሳልፌ፡እሰጣቸዋለሁ ። ፵፯ ጉባኤውም፡በድንጋይ፡ይወግሩአቸዋል፡በሰይፋቸውም፡ይቈርጡአቸዋል÷ወንዶችና፡ሴቶች፡ልጆቻቸውንም፡ይገድላሉ÷ቤቶቻቸውንም፡በእሳት፡ያቃጥላሉ ። ፵፰ ሴቶችም፡ሁሉ፡እንደ፡ሴሰኝነታችሁ፡እንዳይሠሩ፡ይማሩ፡ዘንድ፡ሴሰኝነትን፡ከምድር፡ላይ፡አጠፋለሁ ። ፵፱ ሴሰኝነታችሁንም፡በላያችሁ፡ላይ፡ይመልሳሉ÷እናንተም፡የጣዖቶቻችሁን፡ኀጢአት፡ትሸከማላችሁ ፤ እኔም፡ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንደ፡ሆንሁ፡ታውቃላችሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ በዘጠነኛው፡ዓመት፡በአሥረኛው፡ወር፡ከወሩም፡በአሥረኛው፡ቀን፡የእግዚአብሔር፡ቃል፡ወደ፡እኔ፡እንዲህ፡ሲል፡መጣ ፡— ፪ የሰው፡ልጅ፡ሆይ÷የዚህን፡ቀን÷የዛሬን፡ቀን፡ስም፡

ጻፍ፤ በዚህ፡ ቀን፡ የባቢሎን፡ ንጉሥ፡ ወደ፡
፫፤ ኢየሩሳሌም፡ ቀረበ። ለዓመፀኛውም፡ ቤት፡
ምሳሌን፡ ተናገር፡ እንዲህም፡ በላቸው፡—
ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡— ጣድ÷
ምንቸቲቱን፡ ጣድ÷ ውኃም፡ ጨምርበት።
፬፤ ቍራጭዋንም÷ መልካሙን፡ ቍራጭ፡ ሁሉ÷
ጭኑንና፡ ወርቹን፡ በእርስዋ፡ ውስጥ፡ ሰብስብ÷
፭፤ የተመረጡትንም፡ አጥንቶች፡ ሙላባት። ከመ
ንጋው፡ የተመረጠውን፡ ውሰድ÷ አጥንቶ
ቹም፡ እንዲበስሉ፡ እንጨት፡ በበታችዋ፡
ማግድ፤ አጥንቶቹም፡ በውስጥዋ፡ ይቀቀሉ።
፮፤ ስለዚህ፡ ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡
ይላል፡— ዝገትዋ፡ ላለባት፡ ዝገትዋም፡ ከእር
ስዋ፡ ላልወጣ፡ ምንቸት÷ ለደም፡ ከተማ፡
ወዮላት! ቍራጭ፡ ቍራጩን፡ አውጣ፤ ዕጣ፡
፯፤ አልወደቀባትም። ደምዋ፡ በውስጥዋ፡ አለ።
በተራቈተ፡ ድንጋይ፡ ላይ፡ አደረገችው፡ እንጂ፡
በአፈር፡ ይከደን፡ ዘንድ፡ በመሬት፡ ላይ፡ አላ
፰፤ ፈሰሰችውም፤ መዓቴን፡ አወጣ፡ ዘንድ÷ በቀ
ሌንም፡ እበቀል፡ ዘንድ÷ ደምዋ፡ እንዳይከደን፡
፱፤ በተራቈተ፡ ድንጋይ፡ ላይ፡ አደረግሁ። ስለዚህ፡
ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡— ለደም፡
ከተማ፡ ወዮላት! እኔ፡ ደግሞ፡ ማገዶዋን፡
፲፤ ታላቅ፡ አደርገዋለሁ። እንጨቱን፡ አብዛ፤
እሳቱን፡ አንድድ፤ ሥጋውን፡ ቀቅል፤ መረ
ቁን፡ አጣፍጠው፤ አጥንቶቹ፡ ይቃጠሉ።
፲፩፤ ትሞቅም፡ ዘንድ፡ ናስዋም፡ ትግል፡ ዘንድ፡
ርኵሰትዋም፡ በውስጥዋ፡ ይቀልጥ፡ ዘንድ፡
ዝገትዋም፡ ይጠፋ፡ ዘንድ፡ ባዶዋን፡ በፍም፡
፲፪፤ ላይ፡ አድርጋት። በከንቱ፡ ደከመች፤ ሆኖም፡
፲፫፤ ዝገትዋ፡ በእሳት፡ ስንኳ፡ አልለቀቀም። በርኵ
ሰትሽ፡ ሴሰኝነት፡ አለ፤ አነጻሁሽ፡ አልነጻ
ሽምና፡ መዓቴን፡ በላይሽ፡ እስክጨርስ፡
ድረስ፡ እንግዲህ፡ ከርኵሰትሽ፡ አትነጺም።
፲፬፤ እኔ፡ እግዚአብሔር፡ ተናግሬአለሁ፤ ይመጣል÷
እኔም፡ አደርገዋለሁ፤ አልመለስም÷ አልራ
ራም÷ አልጸጸትም፤ እንደ፡ መንገድሽና፡ እንደ፡
ሥራሽ፡ ይፈርዱብሻል÷ ይላል፡ ጌታ፡ እግዚ
አብሔር።
፲፭፤ የእግዚአብሔርም፡ ቃል፡ ወደ፡ እኔ፡ እንዲህ፡
፲፮፤ ሲል፡ መጣ፡— የሰው፡ ልጅ፡ ሆይ÷ እነሆ÷
የዓይንህን፡ አምሮት፡ በመቅሠፍት፡ እወስድ
ብሃለሁ፤ አንተም፡ ወይ፡ አትበል፡ አታልቅስም፡
፲፯፤ እንባህንም፡ አትፍሰስ። በቀስታ፡ ተክዝ፤
ለምዋቾችም፡ አታልቅስ÷ መጠምጠሚያህን፡
በራስህ፡ ላይ፡ አድርግ÷ ጫማህንም፡ በእግ
ርህ፡ አጥልቅ÷ ከንፈሮችህንም፡ አትሸፍን፡
፲፰፤ የሰዎችንም፡ እንጀራ፡ አትብላ። እኔም፡ በማ
ለዳ፡ ለሕዝቡ፡ ተናገርሁ÷ ወደ፡ ማታም፡ሚስቴ፡
ሞተች፤ በነጋውም፡ እንደ፡ ታዘዝሁ፡ አደረ
ግሁ።
፲፱፤ ሕዝቡም፡— ይህ፡ የምታደርገው፡ ነገር፡
ለእኛ፡ ምን፡ እንደ፡ ሆነ፡ አትነግረንምን?
፳፤ አሉኝ። እኔም፡ እንዲህ፡ አልኋቸው፡— የእ
ግዚአብሔር፡ ቃል፡ ወደ፡ እኔ፡ እንዲህ፡ ሲል፡
፳፩፤ መጣ፡— ለእስራኤል፡ ቤት፡ ተናገር፡ እንዲ
ህም፡ በል፡— ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡
ይላል፡— እነሆ÷ የኃይላችሁን፡ ትምክሕት÷
የዓይናችሁን፡ አምሮት÷ የነፍሳችሁን፡ ምኞት፡
መቅደሴን፡ አረክሳለሁ፤ ያስቀራችኋቸውም፡
ወንዶችና፡ ሴቶች፡ ልጆቻችሁ፡ በሰይፍ፡ ይወ
፳፪፤ ድቃሉ። እኔም፡ እንዳደረግሁ፡ እናንተ፡ ታደ
ርጋላችሁ፤ ከንፈራችሁን፡ አትሸፍኑም፡ የሰዎ
፳፫፤ ችንም፡ እንጀራ፡ አትበሉም። መጠምጠሚ
ያችሁም፡ በራሳችሁ፡ ጫማችሁም፡ በእግራ
ችሁ፡ ይሆናል፤ ዋይ፡ አትሉም፡ አታለቅሱ
ምም፤ በኃጢአታችሁም፡ ትሰለስላላችሁ÷
፳፬፤ እርስ፡ በርሳችሁም፡ ታንጐራጕራላችሁ። ሕዝቅ
ኤልም፡ ምልክት፡ ይሆናችኋል፤ እርሱ፡ እንዳ
ደረገ፡ ሁሉ፡ እናንተ፡ ታደርጋላችሁ፤ ይህም፡
በመጣ፡ ጊዜ፡ እኔ፡ ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ እንደ፡
ሆንሁ፡ ታውቃላችሁ።
፳፭፤ አንተም፡ የሰው፡ ልጅ፡ ሆይ÷ ኃይላቸውን÷
የተመኩበትንም፡ ደስታ÷ የዓይናቸውን፡ አም
ሮት÷ የነፍሳቸውንም፡ ምኞት÷ ወንዶችና፡
ሴቶች፡ ልጆቻቸውን፡ በወሰድሁባቸው፡ ቀን÷
፳፮፤ በዚያ፡ ቀን፡ ያመለጠው፡ ይህን፡ ነገር፡ በጆ
ሮህ፡ ያሰማ፡ ዘንድ፡ ወደ፡ አንተ፡ ይመጣል።
፳፯፤ በዚያ፡ ቀን፡ አፍህ፡ ላመለጠው፡ ይከፈታል÷
አንተም፡ ትናገራለህ፡ ከዚያ፡ ወዲያም፡ ዲዳ፡
አትሆንም፤ ምልክትም፡ ትሆናቸዋለህ÷ እኔም፡
እግዚአብሔር፡ እንደ፡ ሆንሁ፡ ያውቃሉ።

## ምዕራፍ፡ ፳፭።

፩፤ የእግዚአብሔርም፡ ቃል፡ ወደ፡ እኔ፡ እንዲህ፡
፪፤ ሲል፡ መጣ፡— የሰው፡ ልጅ፡ ሆይ÷ ፊትህን፡
ወደ፡ አሞን፡ ልጆች፡ አቅንተህ፡ ትንቢት፡
፫፤ ተናገርባቸው። ለአሞንም፡ ልጆች፡ እንዲህ፡
በል፡— የጌታን፡ የእግዚአብሔርን፡ ቃል፡
ስሙ፤ ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡—
መቅደሴ፡ በረከሰ፡ ጊዜ፡ የእስራኤልም፡ ምድር፡
ባድማ፡ በሆነች፡ ጊዜ፡ የይሁዳም፡ ቤት፡ በተ
ማረኩ፡ ጊዜ፡ ስለ፡ እነርሱ፡ እሰይ፡ ብለሃልና፡
፬፤ ስለዚህ÷ እነሆ÷ ርስት፡ አድርጌ፡ ለምሥራቅ፡
ልጆች፡ አሳልፌ፡ እሰጥሃለሁ÷ እነርሱም፡
በአንተ፡ ውስጥ፡ ይሰፍራሉ÷ ማደሪያዎቻቸ
ውንም፡ በአንተ፡ ዘንድ፡ ይሠራሉ፤ ፍሬህን፡
፭፤ ይበላሉ፡ ወተትህንም፡ ይጠጣሉ። የአሞንን፡
ከተማ፡ ለግመሎች፡ ማሰማርያ÷ የአሞንንም፡
ልጆች፡ ለመንጋ፡ መመሰጊያ፡ አደርጋለሁ፤
እኔም፡ እግዚአብሔር፡ እንደ፡ ሆንሁ፡ ታውቃ
፮፤ ላችሁ። ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላ
ልና፡— በእጅህ፡ አጨብጭበሃልና÷ በእግር
ህም፡ አሸብሽበሃልና÷ በእስራኤልም፡ ምድር፡
ላይ፡ በነፍስህ፡ ንቀት፡ ሁሉ፡ ደስ፡ ብሎሃልና፡
፯፤ ስለዚህ÷ እነሆ÷ እጄን፡ ዘርግቼብሃለሁ÷ ለአ
ሕዛብም፡ አስበዝብዝሃለሁ÷ ከአሕዛብም፡
ለይቼ፡ እቈርጥሃለሁ÷ ከአገሮችም፡ አጠፋሃ

ለሁ ፡ እፈጅህማለሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃለህ ።

፰ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ሞዓብና ፡ ሴይር ፡— እነሆ ÷ የይሁዳ ፡ ቤት ፡ ፱ ፤ እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ነው ፡ ብለዋልና ፡ ስለ ዚህ ÷ እነሆ ÷ የሞዓብን ፡ ጫንቃ ፡ ከከተሞቹ ÷ በዳርቻው ፡ ካሉት ፡ የምድሩ ፡ ትምክሕት ፡ ከሆ ኑት ፡ ከተሞቹ ÷ ከቤትየሺሞት ÷ ከበአልሜ ፲ ፤ ዎን ÷ ከቂርያታይም ÷ ከአሞን ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ ለምሥራቅ ፡ ልጆች ፡ እከፍታለሁ ። የአሞን ፡ ልጆች ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ እንዳይታሰቡ ፡ ርስት ፡ አድርጌ ፡ እሰጣ ፲፩ ፤ ቸዋለሁ ። በሞዓብም ፡ ላይ ፡ ፍርድን ፡ አደርጋ ለሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።

፲፪ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ኤዶምያስ ፡ በይሁዳ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ በቀል ፡ አድ ርጎአልና ÷ ቂም ፡ ይዞአልና ÷ ብድራትንም ፡ ፲፫ ፤ አስከፍሎአልና ፡ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እጄን ፡ በኤዶምያስ ፡ ላይ ፡ እዘረጋለሁ ፡ ከእርስዋም ፡ ዘንድ ፡ ሰውንና ፡ እን ስሳን ፡ አጠፋለሁ ÷ ከቴማንም ፡ ጀምሮ ፡ በድማ ፡ አደርጋታለሁ ÷ እስከ ፡ ድዳንም ፡ ድረስ ፡ በሰ ፲፬ ፤ ይፍ ፡ ይወድቃሉ ። በሕዝቤ ፡ በእስራኤል ፡ እጅ ፡ ኤዶምያስን ፡ እበቀላለሁ ፤ እንደ ፡ ቍጣ ዬና ፡ እንደ ፡ መዓቴም ፡ መጠን ፡ በኤዶምያስ ፡ ያደርጋሉ ፤ በቀሌንም ፡ ያውቃሉ ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፲፭ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ፍልስጥኤማውያን ፡ በቀልን ፡ አድርገዋልና ÷ በዘወትርም ፡ ጠላትነት ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ በነፍ ፲፮ ፤ ሳቸው ፡ ንቀት ፡ ተበቅለዋልና ፡ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ እጄን ፡ በፍልስጥኤማውያን ፡ ላይ ፡ እዘረጋለሁ ÷ ከሊታውያንንም ፡ እቈርጣለሁ ÷ የበሕሩንም ፡ ፲፯ ፤ ዳር ፡ ቅሬታ ፡ አጠፋለሁ ። በመዓት ፡ መቅሠፍ ትም ፡ ታላቅ ፡ በቀል ፡ አደርግባቸዋለሁ ፤ በቀ ሌንም ፡ በላያቸው ፡ በደረግሁ ፡ ጊዜ ÷ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩ ፤ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በአሥራ ፡ አንደኛው ፡ ዓመት ፡ ከወሩ ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ የእግ ዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ፪ ፤ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ጢሮስ ፡ በኢየ ሩሳሌም ፡ ላይ ፡— እሰይ ÷ የአሕዛብ ፡ በር ፡ የነ በረች ፡ ተሰብራለች ፡ ወደ ፡ እኔም ፡ ተመልሳ ለች ፤ እርስዋ ፡ ፈርሳለችና ፡ እኔ ፡ እሞላለሁ ፡ ፫ ፤ ብላለችና ፡ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እን ዲህ ፡ ይላል ፡— ጢሮስ ፡ ሆይ ÷ እነሆ ÷ በአንቺ ፡ ላይ ፡ ነኝ ÷ ባሕርም ፡ ሞገድዋን ፡ እንደምታ ወጣ ፡ እንዲሁ ፡ ብዙ ፡ አሕዛብን ፡ አወጣብሻ ፬ ፤ ለሁ ። የጢሮስንም ፡ ቅጥሮች ፡ ያጠፋሉ ፡ ግን ቦችዋንም ፡ ያፈርሳሉ ፤ ትቢያዋንም ፡ ከእርስዋ ፡ እፍቃለሁ ÷ የተራቈተ ፡ ድንጋይም ፡ አደርጋ ፭ ፤ ታለሁ ። በባሕር ፡ ውስጥ ፡ የመረብ ፡ ማስጫ ፡ ትሆናለች ፤ እኔ ፡ ተናግሬአለሁና ÷ ይላል ፡ እግ ዚአብሔር ፤ ለአሕዛብም ፡ ብዝበዛ ፡ ትሆናለች ። ፮ ፤ በሜዳ ፡ ያሉትም ፡ ሴቶች ፡ ልጆችዋ ፡ በሰይፍ ፡ ይገደላሉ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።

፯ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— እነሆ ÷ ከሰሜን ፡ የነገሥታት ፡ ንጉሥ ፡ የባቢ ሎንን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆርን ፡ ከፈረሶችና ፡ ከሰረገሎች ፡ ከፈረሰኞችም ፡ ከጉባኤና ፡ ከብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ጋር ፡ በጢሮስ ፡ ላይ ፡ አመጣለሁ ። ፰ ፤ በሜዳ ፡ ያሉትን ፡ ሴቶች ፡ ልጆችሽን ፡ በሰይፍ ፡ ይገድላቸዋል ÷ አምባም ፡ ይሠራብሻል ፡ አፈር ንም ፡ ይደለድልብሻል ፡ ጋሻም ፡ ያነሣብሻል ። ፱ ፤ ማፍረሻውን ፡ በቅጥርሽ ፡ ላይ ፡ ያደርጋል ÷ ግን ፲ ፤ ቦችሽንም ፡ በምሳር ፡ ያፈርሳል ። ከፈረሶቹም ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ትቢያቸው ፡ ይከድንሻል ፤ ሰዎ ችም ፡ በተናደች ፡ ቅጥር ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ እንደ ሚገቡ ፡ እርሱ ፡ በበሮችሽ ፡ ሲገባ ÷ ከፈረሰኞ ችና ፡ ከመንኰራኵሮች ፡ ከሰረገሎችም ፡ ድምፅ ፡ ፲፩ ፤ የተነሣ ፡ ቅጥርሽ ፡ ትናወጣለች ። በፈረሶቹ ፡ ኮቴ ፡ ጎዳናዎችሽን ፡ ሁሉ ፡ ይረመርማል ÷ ሕዝ ብሽንም ፡ በሰይፍ ፡ ይገድላል ÷ የብርታትሽም ፡ ፲፪ ፤ ሐውልት ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ይወድቃል ። ብልጥ ግናሽንም ፡ ይማርካሉ ÷ ሸቀጥሽንም ፡ ይበዝብ ዛሉ ፤ ቅጥርሽንም ፡ ያፈርሳሉ ÷ ተድላ ፡ የምታ ደርጊባቸውን ፡ ቤቶችሽን ፡ ያጠፋሉ ፤ ድንጋ ይሽንና ፡ እንጨትሽን ፡ መሬትሽንም ፡ በባሕር ፡ ፲፫ ፤ ውስጥ ፡ ይጥላሉ ። የዘፋኞችሽንም ፡ ብዛት ፡ ዝም ፡ አሰኛለሁ ፤ የመሰንቆሽም ፡ ድምፅ ፡ ከዚያ ፡ ፲፬ ፤ ወዲያ አይሰማም ። የተራቈተ ፡ ድንጋይ ፡ አደ ርግሻለሁ ፡ የመረብም ፡ ማስጫ ፡ ትሆኛለሽ ፤ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አትሠሪም ፤ እኔ ፡ እግዚአ ብሔር ፡ ተናግሬአለሁና ÷ ይላል ፡ እግዚአብ ሔር ።

፲፭ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጢሮስን ፡ እንዲህ ፡ ይላ ታል ፡— የተወጉት ፡ በነቋረሩ ፡ ጊዜ ÷ በውስ ጥሽ ፡ እልቂት ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ÷ ከውድቀትሽ ፡ ድምፅ ፡ ፲፮ ፤ የተነሣ ፡ ደሴቶች ፡ ይነዋወጡ ፡ የለምን ? የባሕ ርም ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ከዙፋኖቻቸው ፡ ይወር ዳሉ ፤ መጐናጸፊያቸውን ፡ ያወጣሉ ፡ ወርቀ ፡ ዘቦ ፡ ልብሳቸውንም ፡ ያወልቃሉ ፤ መንቀጥቀ ጥን ፡ ለብሰው ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ ይቀመጣሉ ÷ ሁልጊዜም ፡ ይንቀጠቀጣሉ ፡ በአንቺም ፡ ይደነ ፲፯ ፤ ቃሉ ። በአንቺም ፡ ላይ ፡ ሙሾ ፡ ያሞሻሉ ÷ እንዲህም ፡ ይሉሻል ፡— በባሕር ፡ የተቀመጥሽ ፡ በባሕርም ፡ ውስጥ ፡ የጸናሽ ÷ ከሚቀመጡብ ሽም ፡ ጋር ፡ በዙሪያሽ ፡ የሚኖሩትን ፡ ሁሉ ፡ ያስ ፈራሽ ÷ የከበርሽ ፡ ከተማ ፡ ሆይ ÷ እንዴት ፡ ፲፰ ፤ ጠፋሽ ! አሁን ፡ በውድቀትሽ ፡ ቀን ፡ ደሴቶች ፡ ይንቀጠቀጣሉ ÷ በባሕርም ፡ ውስጥ ፡ ያሉ ፡ ደሴ ቶች ፡ ከመጥፋትሽ ፡ የተነሣ ፡ ይደነግጣሉ ።

፲፱ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡—

ሰው ፡ እንደሌለባቸው ፡ ከተሞች ፡ በድማ ፡ ከተማ ፡ በደረግሁሽ ፡ ጊዜ ÷ ቀላዩንም ፡ ባወጣ ሁብሽ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ ውኆችም ፡ በከደኑሽ ፡ ጊዜ ÷ ፳ የቀድሞ ፡ ሕዝብ ፡ ወዳሉበት ፡ ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ ከሚወርዱት ፡ ጋር ፡ አወርድሻለሁ ፤ የማኖርብሽም ፡ እንዳይገኝ ፡ ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ ከሚወርዱ ፡ ጋር ፡ ቀድሞ ፡ በፈረሰችው ፡ ስፍራ ÷ በታችኛይቱ ፡ ምድር ፡ አኖርሻለሁ ፤ ጌጥሽንም በሕያዋን ፡ ምድር ፡ አላኖርም ። ፳፩ ለድንጋጤ ፡ አደርግሻለሁ ፡ እንግዲህም ፡ አትኖሪም ፤ ትፈለጊአለሽ ፡ ለዘላለምም ፡ አትገኚም ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን ፪ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— አንተ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ፫ ሆይ ÷ ስለ ፡ ጢሮስ ፡ ሙሾ ፡ አድርግ ÷ በባሕር ፡ መግቢያ ፡ የምትኖር ፡ በብዙም ፡ ደሴቶች ፡ ላይ ፡ ከሚኖሩ ፡ አሕዛብ ፡ ጋር ፡ ንግድን ፡ የምታደርግ ፡ ጢሮስንም ፡ እንዲህ ፡ በላት ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ጢሮስ ፡ ሆይ ÷ አንቺ ፡— በውበት ፡ ፍጹም ፡ ነኝ ፡ ብለሻል ። ፬ ዳርቻሽ ፡ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ ነው ፤ ሠሪዎችሽ ፡ ፭ ውበትሽን ፡ ፈጽመዋል ። ሳንቃዎችሽን ፡ ሁሉ ፡ ከሳኔር ፡ ጥድ ፡ ሠርተዋል ÷ ደቀልንም ፡ ይሠሩልሽ ፡ ዘንድ ፡ ከሊባኖስ ፡ ዝግባ ፡ ወስደዋል ። ፮ ከባሳን ፡ ኮምበል ፡ መቅዘፊያሽን ፡ ሠርተዋል ÷ በዝሆን ፡ ጥርስ ፡ ከታሸበ ፡ ከኪቲም ፡ ደሴቶች ፡ ፯ ዛፍ ፡ መቀመጫዎችሽን ፡ ሠርተዋል ። ዓላማ ፡ እንዲሆንልሽ ፡ ሸራሽ ፡ ከግብጽ ፡ በፍታና ፡ ከወርቀ ፡ ዘቦ ፡ ተሠርቶአል ÷ መደረቢያሽም ፡ ከኤሊሳ ፡ ደሴቶች ፡ ሰማያዊና ፡ ቀይ ፡ ሐር ፡ ተሠር ፰ ቶአል ። የሲዶናና ፡ የአራድ ፡ ሰዎች ፡ ቀዛፎችሽ ፡ ነበሩ ፤ ጢሮስ ፡ ሆይ ÷ ጥበበኞችሽ ፡ በአንቺ ፡ ዘንድ ፡ ነበሩ ፡ የመርከቦችሽም ፡ መሪዎች ፡ ፱ ነበሩ ። በአንቺ ፡ ውስጥ ፡ የነበሩ ፡ የጌባል ፡ ሽማግሌዎችና ፡ ጥበበኞችዋ ፡ ስብራትሽን ፡ ይጠግኑ ፡ ነበር ፤ ከአንቺም ፡ ጋር ፡ ይነግዱ ፡ ዘንድ ፡ የባሕር ፡ መርከቦች ፡ ሁሉና ፡ መርከበኞ ፲ ቻቸው ፡ በመካከልሽ ፡ ነበሩ ። ፋርስና ፡ ሉድ ፡ ፉጥም ፡ በሠራዊትሽ ፡ ሰልፈኞችሽ ፡ ነበሩ ፤ ጋሻና ፡ ራስ ፡ ቍርም ፡ በአንቺ ፡ ውስጥ ፡ ያንጠለጥሉ ፡ ነበር ፤ እነርሱም ፡ ውበትሽን ፡ ሰጡ ። ፲፩ የአራድ ፡ ሰዎችና ፡ ሠራዊቶችሽ ፡ በቅጥሮችሽ ፡ ላይ ፡ በዙሪያ ፡ ነበሩ ÷ ገማዳውያንም ፡ በግንቦችሽ ፡ ውስጥ ፡ ነበሩ ፤ ጋሻቸውንም ፡ በዙሪያ ፡ በቅጥርሽ ፡ ላይ ፡ አንጠለጠሉ ÷ ውበትሽንም ፡ ፈጽመዋል ።

፲፪ ከብልጥግናሽ ፡ ሁሉ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ተርሴስ ፡ ነጋዴሽ ፡ ነበረች ፤ በብርና ፡ በብረት ፡ በቈርቈሮና ፡ በእርሳስ ፡ ስለ ፡ አንቺ ፡ ሸቀጥ ፡ ፲፫ ይነግዱ ፡ ነበር ። ያዋንና ፡ ቶቤል ፡ ሞሳሕም ፡ ነጋዴዎችሽ ፡ ነበሩ ፤ የሰዎችን ፡ ነፍሳትና ፡ የናሱን ፡ ዕቃ ፡ ስለ ፡ አንቺ ፡ ሸቀጥ ፡ ይነግዱ ፡ ነበር ። ፲፬ ከቴርጋማ ፡ ቤትም ፡ የነበሩት ፡ ሰዎች ፡ በፈረሶችና ፡ በፈረሰኞች ፡ በበቅሎዎችም ፡ ስለ ፡ አንቺ ፡ ሸቀጥ ፡ ይነግዱ ፡ ነበር ። ፲፭ የድዳን ፡ ሰዎች ፡ ነጋዴዎችሽ ፡ ነበሩ ። ብዙ ፡ ደሴቶች ፡ የእጅሽ ፡ ገበያዎች ፡ ነበሩ ፤ ይለውጡ ፡ ዘንድ ፡ የዝሆን ፡ ጥርስና ፡ ዞጲ ፡ አመጡልሽ ። ፲፮ ከሥራሽ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ሶርያ ፡ ነጋዴሽ ፡ ነበረች ፤ በበሉርና ፡ በቀይ ፡ ሐር ፡ በወርቀ ፡ ዘቦም ፡ በጥሩ ፡ በፍታም ፡ በዛጕልም ፡ በቀይ ፡ ዕንቍም ፡ ስለ ፡ አንቺ ፡ ሸቀጥ ፡ ይነግዱ ፡ ነበር ። ፲፯ ይሁዳና ፡ የእስራኤል ፡ ምድር ፡ ነጋዴዎችሽ ፡ ነበሩ ፤ የሚኒትን ፡ስንዴ ፡ ጣፋጭም ፡ እንጐቻ ÷ ማር ፡ ዘይትም ፡ በለሳንም ፡ ስለ ፡ አንቺ ፡ ሸቀጥ ፡ ይነግዱ ፡ ነበር ። ፲፰ ከሥራሽ ፡ ብዛትና ፡ ከብልጥግናሽ ፡ ሁሉ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ደማስቆ ፡ ነጋዴሽ ፡ ነበረች ፤ በኬልቦን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ በነጭም ፡ በግ ፡ ጠጕር ፡ ይነግዱ ፡ ነበር ። ፲፱ ዌንዳንና ፡ ያዋን ፡ ስለ ፡ አንቺ ፡ ሸቀጥ ፡ ይነግዱ ፡ ነበር ፤ ከኡሴል ፡ የተሠራ ፡ ብረትና ፡ ብርጕድ ፡ ቀረፋም ፡ ሸቀጥሽ ፡ ነበረ ። ፳ ድዳን ፡ በከብት ፡ ላይ ፡ ለመቀመጥ ፡ በመረሸት ፡ ነጋዴሽ ፡ ነበረች ። ፳፩ ዓረብና ፡ የቄዳር ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ የእጅሽ ፡ ነጋዴዎች ፡ ነበሩ ፤ በጠቦቶችና ፡ በአውራ ፡ በጎች ፡ በፍየሎችም ፡ በእነዚህ ፡ ከአንቺ ፡ ጋር ፡ ይነግዱ ፡ ነበር ። ፳፪ የሳባና ፡ የራዕማ ፡ ነጋዴዎች ፡ እነዚህ ፡ ነጋዴዎችሽ ፡ ነበሩ ፤ በጥሩ ፡ ሽቶና ፡ በክብር ፡ ድንጋይ ፡ ሁሉ ፡ በወርቅም ፡ ስለ ፡ አንቺ ፡ ሸቀጥ ፡ ይነግዱ ፡ ነበር ። ፳፫ ካራንና ፡ ካኔ ፡ ዔድንም ፡ ነጋዴዎችሽ ፡ ነበሩ ፤ አሦርና ፡ ኪልማድ ፡ ነጋዴዎችሽ ፡ ነበሩ ። ፳፬ እነዚህ ፡ ባማረ ፡ ልብስ ፡ በሰማያዊ ፡ ካባ ፡ በወርቀ ፡ ዘቦም ÷ በዝግባ ፡ በተሠራች ፡ በገመድም ፡ በታሰረች ፡ በግምጃም ፡ በተሞላች ፡ ሳጥን ፡ በገበያሽ ፡ ይነግዱ ፡ ነበር ። ፳፭ የተርሴስ ፡ መርከቦች ፡ ሸቀጥሽን ፡ የሚሸከሙ ፡ ነበሩ ፤ አንቺም ፡ ተሞልተሽ ፡ ነበር ፡ በባሕርም ፡ ውስጥ ፡ እጅግ ፡ ከበርሽ ።

፳፮ ቀዛፊዎችሽ ፡ ወደ ፡ ትልቁ ፡ ውኃ ፡ አመጡሽ ፤ የምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ ሰበረሽ ። ፳፯ ብልጥግናሽና ፡ ሸቀጥሽ ፡ ንግድሽም ፡ መርከበኞችሽም ፡ መርከብ ፡ መሪዎችሽም ፡ ሰባራሽንም ፡ የሚጠግኑ ፡ ነጋዴዎችሽም ፡ በአንቺም ፡ ዘንድ ፡ ያሉ ፡ ሰልፈኞችሽ ፡ ሁሉ ፡ በውስጥሽ ፡ ካሉት ፡ ጉባኤ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ በወደቅሽበት ፡ ቀን ፡ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ ይወድቃሉ ። ፳፰ ከመርከብ ፡ መሪዎች ፡ ጩኸት ፡ ድምፅ ፡ የተነሣ ፡ በዙሪያሽ ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ ይንቀጠቀጣሉ ። ፳፱ ቀዛፊዎችም ፡ ሁሉ ፡ መርከበኞችም ፡ መርከብ ፡ መሪዎችም ፡ ሁሉ ፡ ከመርከቦቻቸው ፡ ይወርዳሉ ፡ በመሬትም ፡ ላይ ፡ ይቆማሉ ፤ ፴ ድምፃቸውንም ፡ በአንቺ ፡ ላይ ፡ ያሰማሉ ÷ ምርር ፡ ብለውም ፡ ይጮኻሉ ÷ በራሳቸውም ፡ ላይ ፡ ትቢያ ፡ ይነሰንሳሉ ÷ በአመድም ፡ ውስጥ ፡ ይንከባለላሉ ፤ ፴፩ ስለ ፡ አንቺም ፡ የራሳቸውን ፡ ጠጕር ፡ ይላጫሉ ፡ ማቅም ፡ ያሸርጣሉ ፡ በነፍስ ፡ ምሬትም ፡ ስለ ፡ አንቺ ፡ መራራ ፡ ልቅሶ ፡ ያለቅሳሉ ። ፴፪ በትካዜያ

ቸውም ፡ ልቅሶ ፡ ያነሡልሻል ፥ ስለ ፡ አንቺም ፡
ሙሾ ፡ ያሞሻሉ ፡ እንዲህም ፡ ይላሉ ፦ በባ
ሕር ፡ መካከል ፡ ጠፍቶ ፡ እንደ ፡ ቀረ ፡ እንደ ፡
፴፫ ጢሮስ ፡ ያለ ፡ ማን ፡ ነው ? ሸቀጥሽ ፡ ከባሕር ፡
በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ አሕዛብን ፡ አጥግበሻል ፤
በብልጥግናሽና ፡ በንግድሽ ፡ ብዛት ፡ የምድርን ፡
፴፬ ነገሥታት ፡ ባለ ፡ ጠጎች ፡ አድርገሻል ። አሁን ፡
ግን ፡ በጥልቅ ፡ ውኃ ፡ ውስጥ ፡ በባሕር ፡ ተሰብ
ረሻል ፡ ንግድሽና ፡ ጉባኤሽ ፡ ሁሉ ፡ በመካከ
፴፭ ልሽ ፡ ወድቀዋል ። በደሴቶች ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡
ተደንቀውብሻል ፥ ነገሥታቶቻቸውም ፡ እጅግ ፡
፴፮ ፈርተዋል ፡ ፊታቸውም ፡ ተለውጦአል ። የአሕ
ዛብ ፡ ነጋዴዎች ፡ አፍዋጨብሽ ፤ አንቺ ፡ ለድን
ጋጤ ፡ ሆነሻል ፥ እስከ ፡ ዘላለምም ፡ አትገኚም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡
፪ ሲል ፡ መጣ ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ የጢሮስን ፡
ገዥ ፡ እንዲህ ፡ በለው ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፦ ልብህ ፡ ኰርቶአል ፡ አን
ተም ፦ እኔ ፡ አምላክ ፡ ነኝ ፥ በእግዚአብሔር ፡
ወንበር ፡ በባሕር ፡ መካከል ፡ ተቀምጫለሁ ፡
ብለሃል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ልብህን ፡ እንደ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ልብ ፡ ብታደርግም ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ ነህ ፡
፫ እንጂ ፡ አምላክ ፡ አይደለህም ። እነሆ ፥ ከዳን
ኤል ፡ ይልቅ ፡ ጥበበኛ ፡ ነህ ፥ ምሥጢርም ፡
፬ ሁሉ ፡ ከአንተ ፡ የተሸሸገ ፡ አይደለም ። በጥበ
ብህና ፡ በማስተዋልህ ፡ ብልጥግናን ፡ ለራስህ ፡
አግኝተሃል ፡ ወርቅና ፡ ብርም ፡ በግምጃ ፡ ቤትህ ፡
፭ ውስጥ ፡ ሰብስበሃል ። በታላቅ ፡ ጥበብህና ፡ በን
ግድህ ፡ ብልጥግናህን ፡ አብዝተሃል ፡ በብልጥግና
፮ ህም ፡ ልብህ ፡ ኰርቶአል ። ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ልብህን ፡ እንደ ፡
፯ እግዚአብሔር ፡ ልብ ፡ አድርገሃልና ፡ ስለዚህ ፥
እነሆ ፥ የሌላ ፡ አገር ፡ ሰዎችን ፥ የአሕዛብን ፡
ጨካኞች ፥ አመጣብሃለሁ ፤ ሰይፋቸውንም ፡
በጥበብህ ፡ ውበት ፡ ላይ ፡ ይመዝዛሉ ፡ ክብርህ
፰ ንም ፡ ያረክሳሉ ። ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ ያወርዱሃል ፤
ተገድለው ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ ትሞ
፱ ታለህ ። በውኑ ፡ በገዳይህ ፡ ፊት ፦ እኔ ፡ አም
ላክ ፡ ነኝ ፡ ትላለህን ? ነገር ፡ ግን ፡ በገዳይህ ፡
እጅ ፡ ሰው ፡ ነህ ፡ እንጂ ፡ አምላክ ፡ አይደለ
፲ ህም ። በእንግዶች ፡ እጅ ፡ ያልተገረዙትን ፡
ሰዎች ፡ ሞት ፡ ትሞታለህ ፤ እኔ ፡ ተናግሬአለ
ሁና ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
፲፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፲፪ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ በጢ
ሮስ ፡ ንጉሥ ፡ ላይ ፡ ሙሾ ፡ አሞሽተህ ፡ እን
ዲህ ፡ በለው ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፦ ጥበብን ፡ የተሞላህ ፡ ውበትህም ፡
፲፫ የተፈጸመ ፡ መደምደሚያ ፡ አንተ ፡ ነህ ። በእ
ግዚአብሔር ፡ ገነት ፡ በዔድን ፡ ነበርህ ፤ የከበረ ፡
ዕንቍስ ፡ ሁሉ ፥ ሰርድዮን ፥ ቶጳዝዮን ፥ አል
ማዝ ፥ ቢረሌ ፥ መረግድ ፥ ኢያስጲድ ፥ ሰን
ፔር ፥ በሉር ፥ የሚያብረቀርቅ ፡ ዕንቍ ፥ ወርቅ ፥
ልብስህ ፡ ነበረ ፤ የከበሮህና ፡ የእንቢልታህ ፡
ሥራ ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ነበረ ፤ በተፈጠርህበት ፡
፲፬ ቀን ፡ ተዘጋጅተው ፡ ነበር ። አንተ ፡ ልትጋርድ ፡
የተቀባህ ፡ ኪሩብ ፡ ነበርህ ፤ በተቀደሰው ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ አኖርሁህ ፤ በእ
፲፭ ሳት ፡ ድንጋዮች ፡ መካከል ፡ ተመላለስህ ። ከተ
ፈጠርህበት ፡ ቀን ፡ ጀምረህ ፡ በደል ፡ እስኪገኝ
፲፮ ብህ ፡ ድረስ ፡ በመንገድህ ፡ ፍጹም ፡ ነበርህ ። በን
ግድህ ፡ ብዛት ፡ ግፍ ፡ በውስጥህ ፡ ተሞላ ፡ ኃጢ
አትንም ፡ ሠራህ ፤ ስለዚህ ፡ እንደ ፡ ርኩስ ፡ ነገር ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ተራራ ፡ ጣልሁህ ፤ የምትጋ
ርድ ፡ ኪሩብ ፡ ሆይ ፥ ከእሳት ፡ ድንጋዮች ፡ መካ
፲፯ ከል ፡ አጠፋሁህ ። በውበትህ ፡ ምክንያት ፡
ልብህ ፡ ኰርቶአል ፤ ከክብርህ ፡ የተነሣ ፡ ጥበብ
ህን ፡ አረከስህ ፤ በምድር ፡ ላይ ፡ ጣልሁህ ፡ ያዩ
ህም ፡ ዘንድ ፡ በነገሥታት ፡ ፊት ፡ ሰጠሁህ ።
፲፰ በበደልህ ፡ ብዛት ፡ በንግድህም ፡ ኃጢአት ፡
መቅደስህን ፡ አረከስህ ፤ ስለዚህ ፡ እሳትን ፡ ከው
ስጥህ ፡ አውጥቻለሁ ፡ እርስዋም ፡ በልታሃለች ፥
በሚያዩህም ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡
፲፱ አመድ ፡ አድርጌሃለሁ ። በአሕዛብም ፡ ውስጥ ፡
የሚያውቁህ ፡ ሁሉ ፡ ይደነቁብሃል ፤ አንተም ፡ ለድ
ንጋጤ ፡ ሆነሃል ፥ እስከ ፡ ዘላለምም ፡ አትገኝም ።
፳ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፳፩ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥
ፊትህን ፡ ወደ ፡ ሲዶና ፡ አቅንተህ ፡ ትንቢት ፡
፳፪ ተናገርበት ፥ እንዲህም ፡ በል ፦ ጌታ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ሲዶና ፡ ሆይ ፥
እነሆ ፥ በአንቺ ፡ ላይ ፡ ነኝ ፥ በውስጥሽም ፡
እከብራለሁ ፤ ፍርድንም ፡ በደረግሁባት ፡ ጊዜ ፡
በተቀደስሁባትም ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡
፳፫ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ። ቸነፈርንም ፡ በእር
ስዋ ፡ ላይ ፥ ደምንም ፡ በጎዳናዋ ፡ እሰድዳለሁ ፤
ከዙሪያዋ ፡ በላይዋ ፡ ባለ ፡ ሰይፍ ፡ የተወጉ ፡
በመካከልዋ ፡ ይወድቃሉ ፤ እኔም ፡ እግዚአብ
፳፬ ሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ። ከእንግዲ
ህም ፡ ወዲያ ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ የሚወጋ ፡
እሾህ ፥ በዙሪያቸውም ፡ ካሉ ፡ ከናቋቸው ፡ ሁሉ ፡
የሚያቈስል ፡ ኵርንችት ፡ አይሆንም ፤ እኔም ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።
፳፭ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ የእ
ስራኤልን ፡ ቤት ፡ ከተበተኑባቸው ፡ አሕዛብ ፡
ዘንድ ፡ በሰበሰብሁ ፡ ጊዜ ፥ በአሕዛብም ፡ ፊት ፡
በተቀደስሁባቸው ፡ ጊዜ ፥ ለባሪያዬ ፡ ለያዕቆብ ፡
፳፮ በሰጠኋት ፡ ምድራቸው ፡ ይቀመጣሉ ። ተዘል
ለውም ፡ ይቀመጡባታል ፤ ቤቶችንም ፡ ይሠ
ራሉ ፡ ወይኑንም ፡ ይተክላሉ ፡ በዙሪያቸውም ፡
ባሉ ፡ በሚንቋቸው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ፍርድን ፡ በደ
ረግሁ ፡ ጊዜ ፡ ተዘልለው ፡ ይቀመጣሉ ፤ እኔም ፡
እግዚአብሔር ፡ አምላካቸው ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡
ያውቃሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

፩ በአሥረኛው ፡ ዓመት ፡ በአሥረኛው ፡ ወር ፡
ከወሩም ፡ በአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ቀን ፡ የእግዚ
አብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡
፪ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ፊትህን ፡ በግብጽ ፡
ንጉሥ ፡ በፈርዖን ፡ ላይ ፡ አድርግ ÷ በእርሱና ፡
፫ በግብጽ ፡ ሁሉ ፡ ላይም ፡ ትንቢት ፡ ተናገር ÷ እን
ዲህም ፡ በል ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— በወንዞች ፡ መካከል ፡ የምትተኛና ፡—
ወንዙ ፡ የእኔ ፡ ነው ፡ ለራሴም ፡ ሠርቼዋለሁ ፡
የምትል ፡ ታላቅ ፡ አዞ ÷ የግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ፈር
፬ ዖን ፡ ሆይ ÷ እነሆ ÷ በአንተ ፡ ላይ ፡ ነኝ ። በመ
ንጋጋህ ፡ መቃጥን ፡ አገባብሃለሁ ÷ የወንዞችህ
ንም ፡ ዓሦች ፡ ወደ ፡ ቅርፊትህ ፡ አጣብቃለሁ ፤
ከወንዞችህም ፡ መካከል ፡ አወጣሃለሁ ÷ የወን
ዞችህም ፡ ዓሦች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ቅርፊትህ ፡ ይጣበ
፭ ቃሉ ። አንተንና ፡ የወንዞችህን ፡ ዓሦች ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ እጥላለሁ ÷ በምድርም ፡
ፊት ፡ ላይ ፡ ትወድቃለህ ፡ እንጂ ፡ አትከማችም ፡
አትሰበሰብም ፤ መብልም ፡ አድርጌ ፡ ለምድር ፡
፮ አራዊትና ፡ ለሰማይ ፡ ወፎች ፡ ሰጥቼሃለሁ ። በግ
ብጽም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡
የሸንበቆ ፡ በትር ፡ ሆነዋልና ፡ እኔ ፡ እግዚአብ
፯ ሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ። በእጅ ፡ በያ
ዙህ ፡ ጊዜ ፡ ተሰበርህ ፡ ጫንቃቸውንም ፡ ሁሉ ፡
አቈሰልህ ፤ በተደገፉብህም ፡ ጊዜ ፡ ተሰበርህ ፡
ወገባቸውንም ፡ ሁሉ ፡ አንቀጠቀጥህ ።

፰ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እነሆ ÷ ሰይፍ ፡ አመጣብሃለሁ ÷ ሰው
ንና ፡ እንስሳንም ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ አጠፋለሁ ።
፱ የግብጽም ፡ ምድር ፡ ባድማና ፡ ውድማ ፡ ትሆና
ለች ÷ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡
ያውቃሉ ፤ አንተ ፡— ወንዙ ፡ የእኔ ፡ ነው ፡ የሠ
፲ ራሁትም ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ ብለሃልና ። ስለዚህ ÷
እነሆ ÷ በአንተና ፡ በወንዞችህ ፡ ላይ ፡ ነኝ ÷ የግ
ብጽንም ፡ ምድር ፡ ከሚግዶል ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ሴዌኔና ፡ እስከ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡
፲፩ ውድማና ፡ ባድማ ፡ አደርጋታለሁ ። የሰው ፡
እግር ፡ አያልፍባትም ፡ የእንስሳም ፡ ኰቴ ፡ አያ
ልፍባትም ÷ እስከ ፡ አርባ ፡ ዓመትም ፡ ድረስ ፡
፲፪ ማንም ፡ አይኖርባትም ። ባድማም ፡ በሆኑ ፡
ምድሮች ፡ መካከል ፡ የግብጽን ፡ ምድር ፡
ባድማ ፡ አደርጋታለሁ ÷ በፈረሱትም ፡ ከተ
ሞች ፡ መካከል ፡ ከተሞችዋ ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡
ፈርሰው ፡ ይቀመጣሉ ፤ ግብጻውያንንም ፡ ወደ ፡
አሕዛብ ፡ እበትናቸዋለሁ ፡ በአገሮችም ፡ እዘራ
ቸዋለሁ ።

፲፫ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ከአርባ ፡ ዓመት ፡ በኋላ ፡ ግብጻውያንን ፡ ከተበ
ተኑባቸው ፡ አሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ እሰበስባለሁ ፤
፲፬ የግብጽንም ፡ ምርኮ ፡ እመልሳለሁ ÷ ወደ ፡ ተወ
ለዱባትም ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ ጳትሮስ ፡ እመልሳቸ
ዋለሁ ፤ በዚያም ፡ የተዋረደች ፡ መንግሥት ፡
ይሆናሉ ። ከሌሎች ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ ፲፭
ይልቅ ፡ የተዋረደች ፡ ትሆናለች ፤ ከእንግዲህ ፡
ወዲያ ፡ በአሕዛብ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ አትልም ፤ በአ
ሕዛብም ፡ ላይ ፡ እንዳይገዙ ፡ አሳንሳቸዋለሁ ።
፲፮ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ እነርሱን ፡ በተከተሉ ፡ ጊዜ ፡
እርስዋ ፡ በደልን ፡ ታሳስባለች ÷ ከእንግዲህም ፡
ወዲያ ፡ መታመኛ ፡ አትሆንላቸውም ፤ እኔም ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።

፲፯ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በሀያ ፡ ሰባተኛው ፡ ዓመት ፡
በመጀመሪያው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በመጀመሪ
ያው ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡
፲፰ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷
የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ሠራዊቱን ፡
በጢሮስ ፡ ላይ ፡ ጽኑ ፡ አገልግሎት ፡ አስገለገለ ፤
ራስ ፡ ሁሉ ፡ የተላጨ ፡ ጫንቃም ፡ ሁሉ ፡ የተ
ላጠ ፡ ሆኖአል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በላይዋ ፡ ስላገለገ
ለው ፡ አገልግሎት ፡ እርሱና ፡ ሠራዊቱ ፡ ደመ
፲፱ ወዝ ፡ ከጢሮስ ፡ አልተቀበሉም ። ስለዚህ ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ የግ
ብጽን ፡ ምድር ፡ ለባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ለናቡከደ
ነፆር ፡ እሰጠዋለሁ ÷ ብዛትዋንም ፡ ይወስዳል ፡
ምርኮዋንም ፡ ይማርካል ፡ ብዝበዛዋንም ፡ ይበ
ዘብዛል ፤ ይህም ፡ ለሠራዊቱ ፡ ደመወዝ ፡ ይሆ
፳ ናል ። ስለ ፡ እኔ ፡ ሠርተዋልና ፡ ስለ ፡ አገልግ
ሎቱ ፡ ደመወዝ ፡ የግብጽን ፡ ምድር ፡ ሰጥቼዋ
ለሁ ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፳፩ በዚያ ፡ ቀን ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ ቀንድን ፡
አበቅላለሁ ÷ በመካከላቸውም ፡ ለአንተ ፡ የተ
ከፈተ ፡ አፍን ፡ እሰጣለሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፪ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ትን
ቢት ፡ ተናገር ፡ እንዲህም ፡ በል ፡— ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ዋይ ! በሉ ÷
፫ ለቀኑ ፡ ወዮ ! ቀኑ ፡ ቅርብ ፡ ነው ÷ የእግዚአብ
ሔር ፡ ቀን ፡ ቅርብ ፡ ነው ÷ የደመና ፡ ቀን ÷ የአ
፬ ሕዛብ ፡ ጊዜ ፡ ይሆናል ። ሰይፍ ፡ በግብጽ ፡ ላይ ፡
ይመጣል ÷ ሁከትም ፡ በኢትዮጵያ ፡ ይሆናል ፤
የተገደሉትም ፡ በግብጽ ፡ ውስጥ ፡ ይወድቃሉ ÷
ብዛትዋንም ፡ ይወስዳሉ ÷ መሠረትዋም ፡ ይፈ
፭ ርሳል ። ኢትዮጵያና ፡ ፉጥ ፡ ሉድም ፡ የተደባ
ለቀም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ኩብም ፡ ቃል ፡ ኪዳን
ንም ፡ የገባችው ፡ ምድር ፡ ልጆች ፡ ከእነርሱ ፡
ጋር ፡ በሰይፍ ፡ ይወድቃሉ ።

፮ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ግብጽን ፡
የሚደግፉ ፡ ይወድቃሉ ÷ የኃይልዋም ፡ ትዕ
ቢት ፡ ይወርዳል ፤ ከሚግዶል ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ሴዌኔ ፡ ድረስ ፡ በእርስዋ ፡ ውስጥ ፡ በሰይፍ ፡
ይወድቃሉ ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።
፯ ባድማም ፡ በሆኑ ፡ አገሮች ፡ መካከል ፡ ባድማ ፡
ይሆናሉ ÷ ከተሞችዋም ፡ በፈረሱ ፡ ከተሞች ፡
፰ መካከል ፡ ይሆናሉ ። እሳትንም ፡ በግብጽ ፡ በነ

፳፫፤ ይፍ ፡ ወድቀው ፡ ተገደሉ ። መቃብራቸው ፡ በጕድጓዱ ፡ በውስጠኛው ፡ ክፍል ፡ ነው ÷ ጉባኤዋም ፡ በመቃብርዋ ፡ ዙሪያ ፡ ነው ፤ በሕያዋን ፡ ምድር ፡ ያስፈሩ ፡ ሁሉ ፡ በሰይፍ ፡ ወድቀው ፡ ተገድለዋል ።

፳፬፤ ኤላምም ፡ በዚያ ፡ አለች ፡ ብዛትዋም ፡ ሁሉ ፡ በመቃብርዋ ፡ ዙሪያ ፡ ነው ፤ በሕያዋን ፡ ምድር ፡ ያስፈሩ ፡ ሁሉ ፡ በሰይፍ ፡ ወድቀው ፡ ተገድለዋል ፡ ሳይገረዙም ፡ ወደ ፡ ታችኛው ፡ ምድር ፡ ወርደዋል ÷ ወደ ፡ ጕድጓድም ፡ ከሚወርዱ ፡ ፳፭፤ ጋር ፡ እፍረታቸውን ፡ ተሸክመዋል ። በተገደሉት ፡ መካከል ፡ ከብዛትዋ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ መኝታን ፡ አድርገውላታል ፤ መቃብርዋ ፡ በዙሪያዋ ፡ ነው ፡ ሁሉም ፡ ያልተገረዙና ፡ በሰይፍ ፡ የተገደሉ ፡ ናቸው ፤ በሕያዋንም ፡ ምድር ፡ ያስፈሩ ፡ ነበር ፡ ወደ ፡ ጕድጓድም ፡ ከሚወርዱ ፡ ጋር ፡ እፍረታቸውን ፡ ተሸክመዋል ÷ በተገደሉትም ፡ መካከል ፡ ተሰጥተዋል ።

፳፮፤ ሞሳሕና ፡ ቶቤል ፡ ብዛታቸውም ፡ ሁሉ ፡ በዚያ ፡ አሉ ፡ መቃብራቸውም ፡ በዙሪያቸው ፡ ነው ፤ ሁሉም ፡ ሳይገረዙ ፡ በሰይፍ ፡ ተገድለዋል ፤ በሕያዋን ፡ ምድር ፡ ያስፈሩ ፡ ነበርና ።

፳፯፤ በሕያዋንም ፡ ምድር ፡ ኃያላኑን ፡ ያስፈሩ ፡ ነበርና ፡ መሣሪያቸውን ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ከወረዱ ÷ ሰይፋቸውንም ፡ ከራሳቸው ፡ በታች ፡ ካደረጉ ÷ ኃጢአታቸውም ፡ በአጥንታቸው ፡ ላይ ፡ ከሆነ ፡ ጋር ፡ ከወደቁ ፡ ካልተገረዙ ፡ ኃያ ፳፰፤ ላን ፡ ጋር ፡ ይተኛሉ ። አንተም ፡ ባልተገረዙት ፡ መካከል ፡ ትሰበራለህ ÷ በሰይፍም ፡ ከተገደሉት ፡ ጋር ፡ ትተኛለህ ።

፳፱፤ ኤዶምያስና ፡ ነገሥታቶችዋ ፡ አለቆችዋም ፡ ሁሉ ፡ በዚያ ፡ አሉ ፤ በሰይፍ ፡ ከተገደሉት ፡ ጋር ፡ በኃይላቸው ፡ ተኝተዋል ፤ ካልተገረዙትና ፡ ወደ ፡ ፴፤ ጕድጓድ ፡ ከሚወርዱ ፡ ጋር ፡ ይተኛሉ ። የሰሜን ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ሲዶናውያንም ፡ ሁሉ ፡ ከተገደሉት ፡ ጋር ፡ ወርደው ፡ በዚያ ፡ አሉ ፤ በኃይላቸውም ፡ ያስፈሩ ፤ በነበረው ፡ ፍርሃት ፡ አፍረዋል ÷ በሰይፍም ፡ ከተገደሉት ፡ ጋር ፡ ሳይገረዙ ፡ ተኝተዋል ÷ ወደ ፡ ጕድጓድም ፡ ከሚወርዱት ፡ ጋር ፡ እፍረታቸውን ፡ ተሸክመዋል ።

፴፩፤ በሰይፍ ፡ የተገደሉ ፡ ፈርዖንና ፡ ሠራዊቱ ፡ ሁሉ ፡ ያዩአቸዋል ፡ ፈርዖንም ፡ ስለ ፡ ብዛቱ ፡ ሁሉ ፡ ይጽናናል ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ ፴፪፤ ሔር ። መፈራቱን ፡ በሕያዋን ፡ ምድር ፡ አድርጌአለሁ ÷ ፈርዖንና ፡ ብዛቱም ፡ ሁሉ ፡ በሰይፍ ፡ በተገደሉት ፡ ባልተገረዙት ፡ መካከል ፡ ይተኛሉ ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፫ ።

፩፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ፪፤ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ለሕዝብህ ፡ ልጆች ፡ ተናገር ፡ እንዲህም ፡ በላቸው ፡— ሰይፍን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በመጣሁ ፡ ጊዜ ÷ የምድር ፡ ሕዝብ ፡ ከመካከላቸው ፡ ሰውን ፡ ወስደው ፡ ለራሳቸው ፡ ጕበኛ ፡ ቢያደርጉ ÷ ፫፤ እርሱም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የመጣውን ፡ ሰይፍ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ መለከትን ፡ ቢነፋ ፡ ሕዝቡንም ፡ ቢያስጠነቅቅ ÷ ፬፤ የመለከቱን ፡ ድምፅ ፡ የሚሰማ ፡ ሰው ፡ ባይጠነቀቅ ÷ ሰይፍ ፡ መጥቶ ፡ ቢወስደው ÷ ደሙ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ። ፭፤ የመለከቱን ፡ ድምፅ ፡ ሰምቶ ፡ ስላልተጠነቀቀ ፡ ደሙ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፤ ቢጠነቀቅስ ፡ ኖሮ ፡ ነፍሱን ፡ ባዳነ ፡ ነበር ። ፮፤ ጕበኛው ፡ ግን ፡ ሰይፍ ፡ ሲመጣ ፡ ቢያይ ፡ መለከቱንም ፡ ባይነፋ ፡ ሕዝቡንም ፡ ባያስጠነቅቅ ፡ ሰይፍም ፡ መጥቶ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ከእነርሱ ፡ ቢወስድ ÷ እርሱ ፡ በኃጢአቱ ፡ ተወስዶአል ፡ ደሙን ፡ ግን ፡ ከጕበኛው ፡ እጅ ፡ እፈልጋለሁ ።

፯፤ አንተም ÷ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ ጕበኛ ፡ አድርጌሃለሁ ፤ ከአፌ ፡ ቃሌን ፡ ፰፤ ስማ ፡ ከእኔም ፡ ዘንድ ፡ አስጠንቅቃቸው ። ኃጢአተኛውን ፡— ኃጢአተኛ ፡ ሆይ ÷ በእርግጥ ፡ ትሞታለህ ፡ ባልሁ ፡ ጊዜ ÷ ኃጢአተኛውን ፡ ከመንገዱ ፡ ታስጠነቅቅ ፡ ዘንድ ፡ ባትናገር ፡ ያ ፡ ኃጢአተኛ ፡ በኃጢአቱ ፡ ይሞታል ÷ ደሙን ፡ ፱፤ ግን ፡ ከእጅህ ፡ እፈልጋለሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ ከመንገዱ ፡ ይመለስ ፡ ዘንድ ፡ ኃጢአተኛውን ፡ ብታስጠነቅቀው ፡ እርሱም ፡ ከመንገዱ ፡ ባይመለስ ÷ በኃጢአቱ ፡ ይሞታል ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ነፍስህን ፡ አድነሃል ።

፲፤ አንተም ÷ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ የእስራኤልን ፡ ቤት ፡— እናንተ ፡— በደላችንና ፡ ኃጢአታችን ፡ በላያችን ፡ አሉ ፡ እኛም ፡ ሰልስለን ፡ በቸዋል ፤ እንዴትስ ፡ በሕይወት ፡ እንኖራለን? ፲፩፤ ብላችሁ ፡ ተናግራችኋል ፡ በላቸው ። እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ ኃጢአተኛው ፡ ከመንገዱ ፡ ተመልሶ ፡ በሕይወት ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ እንጂ ፡ ኃጢአተኛው ፡ ይሞት ፡ ዘንድ ፡ አልፈቅድም ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ ተመለሱ ÷ ከክፉ ፡ መንገዳችሁ ፡ ተመለሱ ፤ ስለ ፡ ምንስ ፡ ትሞታላችሁ ? በላቸው ። ፲፪፤ አንተም ÷ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ የሕዝብህን ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ በላቸው ፡— በበደለበት ፡ ቀን ፡ የጻድቅ ፡ ጽድቁ ፡ አያድነውም ÷ ኃጢአተኛም ፡ ከኃጢአቱ ፡ በተመለሰበት ፡ ቀን ፡ በኃጢአቱ ፡ አይሰናከልም ፤ ጻድቁም ፡ ኃጢአት ፡ በሠራበት ፡ ቀን ፡ በጽድቁ ፡ በሕይወት ፡ አይኖ ፲፫፤ ርም ። እኔ ፡ ጻድቁን ፡— በእርግጥ ፡ በሕይወት ፡ ትኖራለህ ፡ ባልሁ ፡ ጊዜ ÷ እርሱ ፡ በጽድቁ ፡ ታምኖ ፡ ኃጢአት ፡ ቢሠራ ፡ በሠራው ፡ ኃጢአት ፡ ይሞታል ፡ እንጂ ፡ ጽድቁ ፡ አይታሰብለ ፲፬፤ ትም ። እኔም ፡ ኃጢአተኛውን ፡— በእርግጥ ፡ ትሞታለህ ፡ ባልሁ ፡ ጊዜ ÷ እርሱ ፡ ከኃጢአቱ ፡ ተመልሶ ፡ ፍርድንና ፡ ቅን ፡ ነገርን ፡ ቢያደርግ ÷ ፲፭፤ ኃጢአተኛውም ፡ መያዣን ፡ ቢመልስ ፡ የነጠቀውንም ፡ ቢመልስ ፡ በሕይወትም ፡ ትእዛዝ ፡ ቢሄድ ፡ ኃጢአትም ፡ ባይሠራ ÷ በሕይወት ፡ ፲፮፤ ይኖራል ፡ እንጂ ፡ አይሞትም ። የሠራው ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ አይታሰብበትም ፤ ፍርድንና ፡ ቅን ፡

ነገርን ፡ አድርጎአል ፤ በእርግጥ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራል ።

፲፯ ነገር ፡ ግን ፡ የሕዝብህ ፡ ልጆች ፡— የጌታ ፡ መንገድ ፡ የቀና ፡ አይደለም ፡ ይላሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ፲፰ የእነርሱ ፡ መንገድ ፡ የቀና ፡ አይደለም ። ጻድቅ ፡ ከጽድቁ ፡ ተመልሶ ፡ ኃጢአትን ፡ ቢሠራ ፡ ይሞ ፲፱ ትበታል ። ኃጢአተኛውም ፡ ከኃጢአቱ ፡ ተመልሶ ፡ ፍርድንና ፡ ቅን ፡ ነገርን ፡ ቢያደርግ ፡ በሕ ፳ ይወት ፡ ይኖርበታል ። እናንተ ፡ ግን ፡— የጌታ ፡ መንገድ ፡ የቀና ፡ አይደለም ፡ ትላላችሁ ። የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ በእያንዳንዳችሁ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ መንገዳችሁ ፡ እፈርድባችኋለሁ ።

፳፩ እንዲህም ፡ ሆነ ፤ በተማረክን ፡ በአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ በአሥረኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአምስተኛው ፡ ቀን ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ያመለጠ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጥቶ ፡— ከተማይቱ ፡ ፳፪ ተመታች ፡ አለኝ ። ያመለጠውም ፡ ሳይመጣ ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ነበረች ÷ በነጋውም ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ አፌን ፡ ከፈተ ፤ አፌም ፡ ተከፈተች ፡ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እኔ ፡ ዲዳ ፡ አልሆንሁም ።

፳፫ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ፳፬ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ በእስራኤል ፡ ምድር ፡ ባሉ ፡ በበድማ ፡ ስፍራዎች ፡ የተቀመጡ ፡— አብርሃም ፡ ብቻውን ፡ ሳለ ፡ ምድሪቱን ፡ ወረሰ ፤ እኛም ፡ ብዙዎች ፡ ነን ፡ ምድሪቱም ፡ ርስት ፡ ሆና ፡ ለእኛ ፡ ተሰጥታለች ፡ ይላሉ ።

፳፭ ስለዚህ ፡ እንዲህ ፡ በላቸው ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ከደም ፡ ጋር ፡ ትበላላችሁ ÷ ዓይናችሁንም ፡ ወደ ፡ ጣዖቶቻችሁ ፡ ታነሣላችሁ ÷ ደምንም ፡ ታፈስሳላችሁ ፤ በውኑ ፡ ፳፮ ምድሪቱን ፡ ትወርሳላችሁን ? ሰይፋችሁን ፡ ይዛችሁ ፡ ቆማችኋል ÷ ርኩስ ፡ ነገርን ፡ ታደርጋላችሁ ÷ የባልንጀሮቻችሁንም ፡ ሚስቶች ፡ ታስነውራላችሁ ፤ በውኑ ፡ ምድሪቱን ፡ ትወርሳላች ፳፯ ሁን ? እንዲህም ፡ በላቸው ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ በበድማ ፡ ስፍራዎች ፡ ያሉ ፡ በሰይፍ ፡ ይወድቃሉ ÷ በምድረ ፡ በዳ ፡ ያለውን ፡ ለአራዊት ፡ መብል ፡ አድርጌ ፡ እሰጣለሁ ÷ በአምባዎችና ፡ ፳፰ በዋሻ ፡ ያሉ ፡ በቸነፈር ፡ ይሞታሉ ። ምድሪቱንም ፡ በድማና ፡ ውድማ ፡ አደርጋታለሁ ፡ የኃይልዋም ፡ ትዕቢት ፡ ይቀራል ÷ የእስራኤልም ፡ ተራሮች ፡ በድማ ፡ ይሆናሉ ÷ ማንም ፡ አያ ፳፱ ልፍባቸውም ። ስላደረጉትም ፡ ርኵሰት ፡ ሁሉ ፡ ምድሪቱን ፡ በድማና ፡ ውድማ ፡ በደረግሁ ፡ ጊዜ ÷ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።

፴ አንተም ÷ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ የሕዝብህ ፡ ልጆች ፡ በቅጥር ፡ አጠገብና ፡ በቤት ፡ ደጆች ፡ ውስጥ ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ ይናገራሉ ÷ እርስ ፡ በርሳቸውም ÷ አንዱ ፡ ከአንዱ ፡ ጋር ፡— እንሂድና ፡ እግዚአብሔር ፡ ያለው ፡ ቃል ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ፴፩ ሆነ ፡ እንስማ ፡ ብለው ፡ ይናገራሉ ። ሕዝብ ፡ እንደሚመጣ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ይመጣሉ ÷ እንደ ፡ ሕዝቤም ፡ በፊትህ ፡ ይቀመጣሉ ÷ ቃልህንም ፡ ይሰማሉ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አያደርጉትም ፤ በአፉቸው ፡ ብዙ ፡ ፍቅር ፡ ይገልጣሉ ÷ ልባቸው ፡ ግን ፡ ስስታቸውን ፡ ትከተላለች ። ፴፪ እነሆ ÷ አንተ ፡ መልካም ፡ ድምፅ ፡ እንዳለው ፡ እንደሚወደድ ፡ መዝሙር ፡ ማለፊያም ፡ አድርጎ ፡ በገና ፡ እንደሚጫወት ፡ ሰው ፡ ሆነህላቸዋል ፤ ቃልህንም ፡ ይሰማሉ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አያደርጉትም ። ፴፫ እነሆ ÷ ይህ ፡ ይመጣል ፤ በመጣም ፡ ጊዜ ፡ እነርሱ ፡ ነቢይ ፡ በመካከላቸው ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ያውቃሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፬ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ፪ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ትንቢት ፡ ተናገር ÷ በእስራኤል ፡ እረኞች ፡ ላይ ፡ ትንቢት ፡ ተናገር ÷ እረኞችንም ፡ እንዲህ ፡ በላቸው ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ራሳቸውን ፡ ለሚያሰማሩ ፡ ለእስራኤል ፡ እረኞች ፡ ወዮላቸው ! እረኞች ፡ በጎችን ፡ ያሰማሩ ፡ ዘንድ ፡ ፫ አይገባቸውምን ? ጮማውን ፡ ትበላላችሁ ፡ ጠጕሩንም ፡ ትለብሳላችሁ ÷ የወፈሩትን ፡ ታርዳላችሁ ፤ በጎቹን ፡ ግን ፡ አታሰማሩም ። ፬ የደከመውን ፡ አላጸናችሁትም ፡ የታመመውንም ፡ አላከማችሁትም ፡ የተሰበረውንም ፡ አልጠገናችሁትም ፡ የባዘነውንም ፡ አልመለሳችሁትም ፡ የጠፋውንም ፡ አልፈለጋችሁትም ፡ በኃይልና ፡ በጭቈናም ፡ ገዛችኋቸው ። ፭ እረኛንም ፡ በማጣት ፡ ተበተኑ ÷ ለምድርም ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ፡ መብል ፡ ሆኑ ÷ ተበተኑም ። ፮ በጎቼ ፡ በተራሮች ፡ ሁሉና ፡ በረዘሙ ፡ ኮረብቶች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ተቅበዘበዙ ÷ በጎቼም ፡ በምድር ፡ ፊት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ተበትነዋል ፤ የሚሻም ፡ የሚፈልግም ፡ አልነበረም ።

፯ ስለዚህ ÷ እረኞች ፡ ሆይ ÷ የእግዚአብሔርን ፡ ፰ ቃል ፡ ስሙ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ እረኛ ፡ ስለሌለ ፡ እረኞቼም ፡ በጎቼን ፡ ስላልፈለጉ ፡ እረኞችም ፡ ራሳቸውን ፡ እንጂ ፡ በጎቼን ፡ ስላላሰማሩ ÷ በጎቼ ፡ ንጥቂያ ፡ ሆነዋልና ÷ በጎቼም ፡ ለምድር ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ፡ መብል ፡ ሆነዋልና ፡ ፱ ስለዚህ ÷ እረኞች ፡ ሆይ ÷ የእግዚአብሔርን ፡ ፲ ቃል ፡ ስሙ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ በእረኞች ፡ ላይ ፡ ነኝ ÷ በጎቼንም ፡ ከእጃቸው ፡ እፈልጋለሁ ÷ በጎቼንም ፡ ከማሰማራት ፡ አስተዋቸዋለሁ ። ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ እረኞች ፡ ራሳቸውን ፡ አያሰማሩም ፤ በጎቼንም ፡ ከአፋቸው ፡ አድናለሁ ÷ መብልም ፡ አይሆኑላቸውም ።

፲፩ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— እነሆ ÷ እኔ ፡ ራሴ ፡ በጎቼን ፡ እሻለሁ ፡ እፈልግማ ፲፪ ለሁ ። እረኛ ፡ በተበተኑት ፡ በጎች ፡ መካከል ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ መንጋውን ፡ እንደሚፈልግ ÷ እንዲሁ ፡ በጎቼን ፡ እፈልጋለሁ ፤ በደመናና ፡ በጨለማ ፡

ቀን፡ከተበተኑት፡ስፍራ፡ሁሉ፡አድናቸዋለሁ።
፲፫ ከአሕዛብም ፡ ዘንድ ፡ አወጣቸዋለሁ፡ ከአገሮ
ችም፡ እሰበስባቸዋለሁ ፥ ወደ፡ገዛ፡ አገራቸ
ውም ፡ አመጣቸዋለሁ ፤ በእስራኤልም ፡ ተራ
ሮች፡ላይ፡በፈሳሾችም፡ አጠገብ፡ በምድርም፡
ላይ፡ ሰዎች፡ በሚኖሩበት፡ ስፍራ ፡ ሁሉ፡ አሰ
፲፬ ማራቸዋለሁ ። በመልካም፡ ማሰማርያ፡ አሰማ
ራቸዋለሁ፡ ጕረኖአቸውም ፡ በረጅሞቹ ፡ በእ
ስራኤል ፡ ተራሮች ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፤ በዚያ፡
በመልካም፡ ጕረኖ፡ ውስጥ፡ ይመሰጋሉ ፥ በእ
ስራኤልም ፡ ተራሮች፡ ላይ፡ በለመለመ፡ ማሰ
፲፭ ማርያ፡ ይሰማራሉ ። እኔ፡ ራሴ፡ በጎቼን፡ አሰ
ማራለሁ፡ አስመስጋቸውማለሁ ፥ ይላል፡ ጌታ፡
፲፮ እግዚአብሔር ። የጠፋውንም ፡ እፈልጋለሁ፡
የባዘነውንም፡ እመልሳለሁ፡ የተሰበረውንም፡
እጠግናለሁ፡ የደከመውንም፡ አጸናለሁ ፤ የወ
ፈረውንና፡ የበረታውንም፡ አጠፋለሁ ፤ በፍር
ድም፡ እጠብቃቸዋለሁ ።

፲፯ ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል ፥— እና
ንተም፡መንጋዬ፡ሆይ ፥ እነሆ ፥ በበግና፡በበግ ፡
መከከል ፥ በአውራ፡በግና፡በአውራ፡ፍየልም፡
፲፰ መከከል ፥ እፈርዳለሁ ። የቀረውን ፡ ማሰማር
ያችሁን ፡ በእግራችሁ ፡ የረገጣችሁት ፥ በመ
ልካሙ ፡ ማሰማርያ፡ መሰማራታችሁ፡ ባይበቃ
ችሁ፡ ነውን? የቀረውንስ፡ ውኃ፡ በእግራችሁ፡
ያደፈረሳችሁት ፥ ጥሩውን፡ ውኃ፡ መጠጣታ
፲፱ ችሁ ፡ ባይበቃችሁ፡ ነውን ? በጎቼም፡ በእግ
ራችሁ፡ በረገጣችሁት ፡ ይሰማራሉ ፡ በእግራ
ችሁም ፡ ያደፈረሳችሁትን፡ ይጠጣሉ ።

፳ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላቸዋል ፥— እነሆ ፥ እኔ፡ በወፈሩት ፡ በጎችና፡
፳፩ በከሱት ፡ በጎች፡ መካከል ፡ እፈርዳለሁ ። እስክ
ትበትኑአቸው ፡ ድረስ ፡ በእንቢያና ፡ በትከሻ ፡
ስለምትገፉአቸው ፡ የደከሙትንም፡ ሁሉ ፡ በቀ
፳፪ ንዳችሁ ፡ ስለምትወጉአቸው ፥ ስለዚህ፡ መን
ጋዬን ፡ አድናለሁ ፥ ከእንግዲህ፡ ወዲህም፡ ንጥ
ቂያ፡ አይሆኑም ፤ በበግና ፡ በበግ፡ መካከልም፡
፳፫ እፈርዳለሁ ። በላያቸውም፡ አንድ፡ እረኛ፡ አቆ
ማለሁ ፡ እርሱም ፡ ያሰማራቸዋል ፥ እርሱም፡
ባሪያዬ፡ዳዊት፡ነው ፤ ያሰማራቸዋል፡ እረኛም፡
፳፬ ይሆናቸዋል ። እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ አም
ላክ ፡ እሆናቸዋለሁ ፡ ባሪያዬም ፡ ዳዊት ፡ በመካ
ከላቸው ፡ አለቃ ፡ ይሆናል ፤ እኔ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ተናግሬአለሁ ።

፳፭ የሰላምን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ከእነርሱ፡ ጋር፡ እጋ
ባለሁ ፡ ክፉዎችንም፡ አራዊት፡ ከምድር፡ አጠፋ
ለሁ ፤ ተዘልለውም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ይኖራሉ፡
፳፮ በዱርም ፡ ውስጥ ፡ ይተኛሉ ። እነርሱንና፡ በኮ
ረብታዬ ፡ ዙሪያ ፡ ያሉትን ፡ ስፍራዎች ፡ ለበረ
ከት ፡ አደርጋቸዋለሁ ፥ ዝናቡንም ፡ በጊዜው ፡
አወርዳለሁ ፤ የበረከት ፡ ዝናብ ፡ ይሆናል ።
፳፯ የምድረ ፡ በዳም ፡ ዛፍ ፡ ፍሬውን ፡ ይሰጣል ፡
ምድርም ፡ ቡቃያዋን ፡ ትሰጣለች ፥ በምድራቸ
ውም ፡ ተዘልለው ፡ ይኖራሉ ፤ የቀንበራቸው
ንም ፡ ማነቆ ፡ በሰበርሁ ፡ ጊዜ ፡ ከሚገዙአቸ
ውም ፡ እጅ ፡ ባዳንኋቸው ፡ ጊዜ ፥ እኔ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ። እንግዲ ፳፰
ህም ፡ ለአሕዛብ ፡ ንጥቂያ ፡ አይሆኑም ፡ የምድ
ርም ፡ አራዊት ፡ አይበሉአቸውም ፤ ተዘልለ
ውም፡ይቀመጣሉ፡የሚያስፈራቸውም፡የለም።
የዝናን፡ ተክል፡ አቆምላቸዋለሁ፡ እንግዲህም፡ ፳፱
ከራብ፡ የተነሣ፡ በምድር፡ አያልቁም ፤ የአሕዛ
ብንም ፡ ስድብ ፡ ከእንግዲህ፡ ወዲህ፡ አይሸከ
ሙም ። እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካቸው ፡ ፴
ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ እንዳለሁ ፥ እነርሱም ፡ የእስራ
ኤል ፡ ቤት ፡ ሕዝቤ ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ያውቃሉ ፥
ይላል፡ ጌታ፡እግዚአብሔር። እናንተም፡ በጎቼ ፥ ፴፩
የማሰማርያዬ ፡ በጎች ፥ ሰዎች ፡ ናችሁ ፡ እኔም ፡
አምላካችሁ ፡ ነኝ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፭ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ፡ እኔ ፡ እን
፪ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፥— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥
ፊትህን ፡ ወደ ፡ ሴይር ፡ ተራራ ፡ አድርግ ፥ ትን
፫ ቢትም ፡ ተናገርበት ፥ እንዲህም ፡ በለው ፥—
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፥— የሴ
ይር ፡ ተራራ ፡ ሆይ ፥ እነሆ ፥ በአንተ ፡ ላይ ፡
ነኝ ፥ እጄንም፡ እዘረጋብሃለሁ፡ ባድማና፡ ውድ
፬ ማም ፡ አደርግሃለሁ ። ከተሞችህንም ፡ አፈራር
ሳቸዋለሁ ፥ አንተም ፡ ባድማ ፡ ትሆናለህ ፥
እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታው
፭ ቃለህ ። የዘላለም ፡ ጥል ፡ ስላለህ ፡ በመከራቸ
ውም ፡ ጊዜ ፡ በኋለኛይቱ ፡ የኃጢአታቸው ፡
ቀጠሮ ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ በሰይፍ ፡
፮ እጅ ፡ ጥለሃቸዋልና ፡ ስለዚህ ፡ እኔ ፡ ሕያው ፡
ነኝና ፡ ለደም ፡ አሳልፌ ፡ እሰጥሃለሁ ፡ ደምም ፡
ያሳድድሃል ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤
፯ ደምን ፡ ስላልጠላህ ፡ ደም ፡ ያሳድድሃል ። የሴይ
ርንም ፡ ተራራ ፡ ውድማ ፡ አደርገዋለሁ ፥ የሚ
ሄደውንና ፡ የሚመለሰውንም ፡ ከእርሱ ፡ አጠፋ
፰ ለሁ ። ተራሮቹንም ፡ በተገደሉት ፡ ሰዎች ፡ እሞ
ላለሁ ፤ በኮረብቶችህና ፡ በሸለቆችህ ፡ በፈሳሾች
ህም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በሰይፍ ፡ የተገደሉት ፡ ሁሉ ፡
፱ ይወድቃሉ ። ለዘላለምም ፡ ባድማ ፡ አደርግሃ
ለሁ ፡ ከተሞችህም ፡ ሰው ፡ የማይኖርባቸው ፡
ይሆናሉ ፥ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡
ታውቃላችሁ ።

፲ እግዚአብሔርም ፡ በዚያ ፡ ሳለ ፥ አንተ ፥— እነ
ዚህ ፡ ሁለቱ ፡ ሕዝቦች ፡ እነዚህም ፡ ሁለቱ ፡ አገ
ሮች ፡ ለእኔ ፡ ይሆናሉ ፡ እኛም ፡ እንወርሳቸዋለን ፡
፲፩ ብለሃልና ፡ ስለዚህ ፡ እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ እንደ ፡
ቍጣህ ፡ መጠን ፡ እነርሱንም ፡ ጠልተህ ፡ እንዳ
ደረግኸው ፡ እንደ ፡ ቅንዓትህ ፡ መጠን ፡ እኔ ፡
እሠራለሁ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ በፈ
ረድሁብህም ፡ ጊዜ ፡ በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ የታወ
፲፪ ቅሁ ፡ እሆናለሁ ። አንተም ፥— ፈርሰዋል ፡ መብ
ልም ፡ ሆነው ፡ ለእኛ ፡ ተሰጥተዋል ፡ ብለህ ፡

በእስራኤል ፡ ተራሮች ፡ ላይ ፡ የተናገርኸውን ፡
ስድብ ፡ ሁሉ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሰማ
፲፫ ሁት ፡ ታውቃለህ ። በአፋችሁም ፡ ተመካችሁ
ብኝ ፥ ቃላችሁንም ፡ አበዛችሁብኝ ፤ እኔ ፡ ሰም
፲፬ ቼዋለሁ ። ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፦ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ሲላት ፡ አንተን ፡
፲፭ ባድማ ፡ አደርግሃለሁ ። የእስራኤል ፡ ቤት ፡
ርስት ፡ ባድማ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በላዩ ፡ ደስ ፡ እን
ዳለህ ፥ እንዲሁ ፡ አደርግብሃለሁ ፤ የሴይር ፡
ተራራ ፡ ሆይ ፥ አንተና ፡ ኤዶምያስ ፡ ሁሉ ፡
ሁለንተናውም ፡ ባድማ ፡ ትሆናላችሁ ፤ እኔም ፡
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፮ ።

፩ አንተም ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ለእስራኤል ፡
ተራሮች ፡ ትንቢት ፡ ተናግረህ ፦ የእስራኤል ፡
ተራሮች ፡ ሆይ ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
፪ ስሙ ፡ በል ። ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፦ ጠላት ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፦ እሰይ ፥
የጥንት ፡ ከፍታዎች ፡ ለእኛ ፡ ርስት ፡ ሆነዋል ፡
፫ ብሎአልና ፡ ስለዚህ ፡ ትንቢት ፡ ተናገር ፡ እን
ዲህም ፡ በል ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፦ ለቀሩት ፡ አሕዛብ ፡ ርስት ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ፡
በዙሪያችሁ ፡ ያሉ ፡ ባድማ ፡ አድርገዋችኋልና ፥
ውጠዋችሁማልና ፥ እናንተም ፡ የተናጋሪዎች ፡
ከንፈር ፡ መተረቻና ፡ የአሕዛብ ፡ ማላገጫ ፡ ሆና
፬ ችኋልና ፡ ስለዚህ ፥ እናንተ ፡ የእስራኤል ፡ ተራ
ሮች ፡ ሆይ ፥ የጌታን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
ስሙ ። ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለተራሮችና ፡
ለኮረብቶች ፥ ለፈሳሾችና ፡ ለሸለቆች ፡ ለም
ድረ ፡ በዳዎች ፡ ባዶ ፡ ለሆኑትም ፡ በዙሪያ ፡
ላሉት ፡ ለቀሩት ፡ አሕዛብ ፡ ምርኮና ፡ መሳቂያ ፡
፭ ለሆኑት ፡ ከተሞች ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፤ ስለዚህ ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ያሳ
ድዱአትና ፡ ይበዘብዙአት ፡ ዘንድ ፡ በልባቸው ፡
ሁሉ ፡ ደስታና ፡ በነፍሳቸው ፡ ንቀት ፡ ምድሬን ፡
ርስት ፡ አድርገው ፡ ለራሳቸው ፡ በሰጡ ፡ በቀ
ሩት ፡ አሕዛብና ፡ በኤዶምያስ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡
፮ በቅንዓቴ ፡ እሳት ፡ ተናግሬአለሁ ፤ ስለዚህ ፡
ስለ ፡ እስራኤል ፡ ምድር ፡ ትንቢት ፡ ተናገር ፥
ለተራሮችና ፡ ለኮረብቶችም ፡ ለፈሳሾችና ፡ ለሸ
ለቆችም ፡ እንዲህ ፡ በል ፦ ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እነሆ ፥ የአሕዛብን ፡
ስድብ ፡ ስለ ፡ ተሸከማችሁ ፡ በቅንዓቴና ፡ በመ
፯ ዓቴ ፡ ተናግሬአለሁ ፤ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ በዙሪያችሁ ፡ ያሉ ፡
አሕዛብ ፡ ስድባቸውን ፡ በእርግጥ ፡ ይሸከማሉ ፡
ብዬ ፡ምያለሁ ።

፰ የእስራኤል ፡ ተራሮች ፡ ሆይ ፥ እናንተ ፡ ግን ፡
ቅርንጫፎቻችሁን ፡ ታቈጠቍጣላችሁ ፥ ይመ
ጡም ፡ ዘንድ ፡ ቀርበዋልና ፡ ለሕዝቤ ፡ ለእስ
፱ ራኤል ፡ ፍሬአችሁን ፡ ትሰጣላችሁ ። እነሆ ፥
እኔ ፡ ለእናንተ ፡ ነኝና ፤ ወደ ፡ እናንተም ፡ እመ
ለከታለሁ ፥ እናንተም ፡ ትታረሳላችሁ ፡ ይዘራ

ባችሁማል ፤ እኔም ፡ የእስራኤልን ፡ ቤት ፡ ሰዎች ፡ ፲
ሁሉ ፡ ሁሉንም ፡ አበዛባችኋለሁ ፥ በከተሞ
ችም ፡ ሰዎች ፡ ይኖሩባቸዋል ፡ ባድማዎቹም ፡
ስፍራዎች ፡ ይሠራሉ ፤ ሰውንና ፡ እንስሳውንም ፡ ፲፩
አበዛባችኋለሁ ፥ እነርሱም ፡ ይበዛሉ ፡ ያፈሩ
ማል ፤ እንደ ፡ ጥንታችሁም ፡ ሰዎችን ፡ አኖርብ
ችኋለሁ ፥ ቀድሞም ፡ ከደረግሁላችሁ ፡ ይልቅ ፡
መልካም ፡ አደርግላችኋለሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ። ሰዎች ፲፪
ንም ፥ ሕዝቤን ፡ እስራኤልን ፥ በእናንተ ፡ ላይ ፡
አስሄዳቸዋለሁ ፤ እነርሱም ፡ ይወርሱሻል ፡ ርስ
ትም ፡ ትሆኛቸዋለሽ ፥ ከእንግዲህም ፡ ወዲያ ፡
ልጅ ፡ አልባ ፡ አታደርጊአቸውም ። ጌታ ፡ እግ ፲፫
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እነርሱ ፦
ሰው ፡ በሊታ ፡ ምድር ፡ ነሽ ፡ ሕዝብሽንም ፡
ልጅ ፡ አልባ ፡ የምታደርጊ ፡ ነሽ ፡ ብለዋችኋ
ልና ፡ ስለዚህ ፡ ዳግመኛ ፡ ሰው ፡ በሊታ ፡ አት ፲፬
ሆኚም ፥ ዳግመኛም ፡ ሕዝብሽን ፡ ልጅ ፡ አልባ ፡
አታደርጊም ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤
ዳግመኛም ፡ የአሕዛብን ፡ ውርደት ፡ አላሰማብ ፲፭
ሽም ፥ ዳግመኛም ፡ የአሕዛብን ፡ ስድብ ፡ አትሸ
ከሚም ፥ ዳግመኛም ፡ ሕዝብሽን ፡ አታሰና
ክዪም ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ፲፮
ሲል ፡ መጣ ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ የእስራ ፲፯
ኤል ፡ ቤት ፡ በምድራቸው ፡ በተቀመጡ ፡ ጊዜ ፡
በመንገዳቸውና ፡ በሥራቸው ፡ አረከሱአት ፥
መንገዳቸውም ፡ በፊቴ ፡ እንደ ፡ መርገም ፡ አደፍ ፡
ነበረ ። በምድር ፡ ላይ ፡ ስላፈሰሱት ፡ ደም ፡ በጣ ፲፰
ዖቶቻቸውም ፡ ስላረከሱአት ፡ መዓቴን ፡ አፈሰ
ስሁባቸው ፤ ወደ ፡ አሕዛብም ፡ በተንኋቸው ፡ ፲፱
ወደ ፡ አገሮችም ፡ ተዘሩ ፤ እንደ ፡ መንገዳቸ
ውና ፡ እንደ ፡ ሥራቸው ፡ መጠን ፡ ፈረድሁብ
ቸው ። ወደ ፡ መጡባቸውም ፡ ወደ ፡ አሕዛብ ፡ ፳
በመጡ ፡ ጊዜ ፥ ሰዎች ፡ እነርሱን ፦ ከምድሩ ፡
የወጡ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡ እነዚህ ፡
ናቸው ፡ ሲሉአቸው ፡ ቅዱስ ፡ ስሜን ፡ አረከሱ ።
እኔ ፡ ግን ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ በመጡባቸው ፡ ፳፩
በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ስላረከሱት ፡ ስለ ፡ ቅዱስ ፡
ስሜ ፡ ስል ፡ ራራሁላቸው ።

ስለዚህ ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ እንዲህ ፡ በል ፦ ፳፪
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ የእስ
ራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ በመጣችሁባቸው ፡ በአ
ሕዛብ ፡ መካከል ፡ ስላረከሳችሁት ፡ ስለ ፡ ቅዱስ ፡
ስሜ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ የምሠራ ፡ አይ
ደለሁም ። በአሕዛብም ፡ ዘንድ ፡ የረከሰውን ፥ ፳፫
በመካከላቸው ፡ ያረከሳችሁትን ፡ ስሜን ፡ አቀ
ድሰዋለሁ ፤ በዓይናቸውም ፡ ዘንድ ፡ በተቀደስ
ሁባችሁ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡
ሆንሁ ፡ አሕዛብ ፡ ያውቃሉ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ። ከአሕዛብም ፡ መካከል ፡ አወጣ ፳፬
ችኋለሁ ፡ ከየአገሩም ፡ ሁሉ ፡ እሰበስባችኋለሁ ፡
ወደ ፡ ገዛ ፡ ምድራችሁም ፡ አመጣችኋለሁ ።
ጥሩ ፡ ውኃንም ፡ እረጭባችኋለሁ ፡ እናንተም ፡ ፳፭

ትጠራላችሁ ፤ ከርኵሰታችሁም ፡ ሁሉ ፡ ከጣዖቶቻችሁም ፡ ሁሉ ፡ አጠራችኋለሁ ። ፳፮ አዲስም ፡ ልብ ፡ እሰጣችኋለሁ ፡ አዲስም ፡ መንፈስ ፡ በውስጣችሁ ፡ አኖራለሁ ፤ የድንጋዩንም ፡ ልብ ፡ ከሥጋችሁ ፡ አወጣለሁ ፡ የሥጋንም ፡ ልብ ፡ እሰጣችኋለሁ ። ፳፯ መንፈሴንም ፡ በውስጣችሁ ፡ አኖራለሁ ፡ በትእዛዜም ፡ አስሄዳችኋለሁ ፤ ፍርዴንም ፡ ትጠብቃላችሁ ፡ ታደርጉትማላችሁ ። ፳፰ ለአባቶቻችሁም ፡ በሰጠኋት ፡ ምድር ፡ ትኖራላችሁ ፤ ሕዝብም ፡ ትሆኑኛላችሁ ፡ እኔም ፡ አምላክ ፡ እሆናችኋለሁ ። ፳፱ ከርኵሰታችሁም ፡ ሁሉ ፡ አድናችኋለሁ ፤ እህልንም ፡ እጠራዋለሁ ፡ አበዛውማለሁ ፡ ራብንም ፡ አላመጣባችሁም ። ፴ ደግሞም ፡ የራብን ፡ ስድብ ፡ ከአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ እንዳትሸከሙ ፡ የዛፍን ፡ ፍሬና ፡ የእርሻውን ፡ ቡቃያ ፡ አበዛለሁ ። ፴፩ ክፉውን ፡ መንገዳችሁንና ፡ መልካም ፡ ያይደለውን ፡ ሥራችሁንም ፡ ታስባላችሁ ፤ ስለ ፡ በደላችሁና ፡ ስለ ፡ ርኵሰታችሁም ፡ ራሳችሁን ፡ ትጸየፋላችሁ ። ፴፪ ይህን ፡ የሠራሁ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ እንዳይደለ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ የታወቀ ፡ ይሁን ፤ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፤ ስለ ፡ መንገዳችሁ ፡ እፈሩና ፡ ተዋረዱ ።

፴፫ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ከኃጢአታችሁ ፡ ሁሉ ፡ በነጻኋችሁበት ፡ ቀን ፡ በከተሞች ፡ ሰዎችን ፡ አኖራለሁ ፡ በድማዎቹም ፡ ስፍራዎች ፡ ይሠራሉ ። ፴፬ በድማ ፡ የነበረች ፡ በመንገደኛም ፡ ሁሉ ፡ ዓይን ፡ ዘንድ ፡ በድማ ፡ የነበረች ፡ ምድር ፡ ትታረሳለች ። ፴፭ ሰዎችም ፦ በድማ ፡ የነበረች ፡ ይህች ፡ ምድር ፡ እንደ ፡ ዔድን ፡ ገነት ፡ ሆናለች ፤ የፈረሱት ፡ በድማ ፡ የሆኑት ፡ የጠፉትም ፡ ከተሞች ፡ ተመሽገዋል ፡ ሰውም ፡ የሚኖርባቸው ፡ ሆነዋል ፡ ይላሉ ። ፴፮ በዙሪያችሁም ፡ የቀሩት ፡ አሕዛብ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ የፈረሱትን ፡ ስፍራዎች ፡ እንደ ፡ ሠራሁ ፡ ውድማ ፡ የሆነውንም ፡ እንደ ፡ ተከልሁ ፡ ያውቃሉ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናግሬአለሁ ፤ እኔም ፡ አደርገዋለሁ ።

፴፯ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ስለዚህ ፡ ደግሞ ፡ አደርግላቸው ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ይሹኛል ፡ ሰውንም ፡ እንደ ፡ መንጋ ፡ አበዛላቸዋለሁ ። ፴፰ እንደ ፡ ተቀደሱ ፡ በጎች ፤ በበዓላቶችዋ ፡ ቀን ፡ እንደሚሆኑ ፡ እንደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በጎች ፤ እንዲሁ ፡ የፈረሱት ፡ ከተሞች ፡ በሰዎች ፡ መንጋ ፡ ይሞላሉ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፯ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ እጅ ፡ በላዬ ፡ ነበረ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በመንፈሱ ፡ አወጣኝ ፡ አጥንቶችም ፡ በሞሉበት ፡ ሸለቆ ፡ መካከል ፡ አኖረኝ ። ፪ በእነርሱም ፡ እንጻር ፡ በዙሪያቸው ፡ አሳለፈኝ ፤ እነሆም ፤ በሸለቆው ፡ ፊት ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነበሩ ፤ እነሆም ፤ እጅግ ፡ ደርቀው ፡ ነበር ። ፫ እርሱም ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፤ እነዚህ ፡ አጥንቶች ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉን ? አለኝ ። እኔም ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፤ አንተ ፡ ታውቃለህ ፡ አልሁ ። ፬ እርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፦ በእነዚህ ፡ አጥንቶች ፡ ላይ ፡ ትንቢት ፡ ተናገር ፡ እንዲህም ፡ በላቸው ፦ እናንተ ፡ የደረቃችሁ ፡ አጥንቶች ፡ ሆይ ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስሙ ። ፭ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእነዚህ ፡ አጥንቶች ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እነሆ ፤ ትንፋሽን ፡ አገባባችኋለሁ ፡ በሕይወትም ፡ ትኖራላችሁ ። ፮ ጅማትም ፡ እሰጣችኋለሁ ፡ ሥጋንም ፡ አወጣባችኋለሁ ፡ በእናንተም ፡ ላይ ፡ ቁርበትን ፡ እዘረጋለሁ ፡ ትንፋሽንም ፡ አገባባችኋለሁ ፡ በሕይወትም ፡ ትኖራላችሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ።

፯ እንዳዘዘኝም ፡ ትንቢት ፡ ተናገርሁ ፤ ስናገርም ፡ ድምፅ ፡ ሆነ ፤ እነሆም ፤ መናወጥ ፡ ሆነ ፤ አጥንቶችም ፡ አጥንት ፡ ከአጥንት ፡ ጋር ፡ ተቀራረቡ ። ፰ እኔም ፡ አየሁ ፤ እነሆም ፤ ጅማት ፡ ነበረባቸው ፡ ሥጋም ፡ ወጣ ፡ ቁርበትም ፡ በላያቸው ፡ ተዘረጋ ፤ ትንፋሽ ፡ ግን ፡ አልነበረባቸውም ። ፱ እርሱም ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፤ ትንቢት ፡ ተናገር ፤ ለነፋስ ፡ ትንቢት ፡ ተናገር ፤ ለነፋስም ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ነፋስ ፡ ሆይ ፤ ከአራቱ ፡ ነፋሳት ፡ ዘንድ ፡ ና ፤ እነዚህም ፡ የተገደሉት ፡ በሕይወት ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡ እፍ ፡ በልባቸው ፡ በል ፡ አለኝ ። ፲ እንዳዘዘኝም ፡ ትንቢት ፡ ተናገርሁ ፤ ትንፋሽም ፡ ገባባቸው ፡ ሕያዋንም ፡ ሆኑ ፤ እጅግም ፡ ታላቅ ፡ ሠራዊት ፡ ሆነው ፡ በእግራቸው ፡ ቆሙ ።

፲፩ እርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፤ እነዚህ ፡ አጥንቶች ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ናቸው ፤ እነሆ ፦ አጥንቶቻችን ፡ ደርቀዋል ፡ ተስፋችንም ፡ ጠፍቶአል ፡ ፈጽመንም ፡ ተቈርጠናል ፡ ብለዋል ። ፲፪ ስለዚህ ፡ ትንቢት ፡ ተናገር ፡ እንዲህም ፡ በላቸው ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ሕዝቤ ፡ ሆይ ፤ እነሆ ፤ መቃብራችሁን ፡ እከፍታለሁ ፡ ከመቃብራችሁም ፡ አወጣችኋለሁ ፤ ወደ ፡ እስራኤልም ፡ ምድር ፡ አገባችኋለሁ ። ፲፫ ሕዝቤ ፡ ሆይ ፤ መቃብራችሁን ፡ በከፈትሁ ፡ ጊዜ ፡ ከመቃብራችሁም ፡ በወጣኋችሁ ፡ ጊዜ ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ። ፲፬ መንፈሴንም ፡ በውስጣችሁ ፡ አሳድራለሁ ፤ እናንተም ፡ በሕይወት ፡ ትኖራላችሁ ፤ በገዛ ፡ ምድራችሁም ፡ አኖራችኋለሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተናገርሁ ፡ እንዳደረግሁም ፡ ታውቃላችሁ ፤ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፲፭ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦ ፲፮ አንተ ፤ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፤ አንድ ፡ በትር ፡ ውሰድና ፦ ለይሁዳና ፡ ለባልንጀሮቹ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ብለህ ፡ በላዩ ፡ ጻፍ ፤ ሌላም ፡ በትር ፡ ውሰድና ፦ የኤ

ፍሬም ፡ በትር ፡ ለዮሴፍና ፡ ለባልንጀሮቹ ፡ ለእ ስራኤል ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ብለህ ፡ በላዩ ፡ጻፍ ። ፲፯ አንድ ፡ በትርም ፡ እንዲሆኑ ፡ አንዱን ፡ ከሁለተ ኛው ፡ ጋር ፡ ለአንተ ፡ አጋጥም ÷ በእጅህም ፡ ውስጥ፡አንድ፡ይሁኑ ። ፲፰ የሕዝብህም፡ልጆች ፡— ይህ፡የምታደርገው፡ነገር፡ምን፡ማለት፡እንደ፡ ሆነ፡አትነግረንምን?ብለው፡በተናገሩህ፡ጊዜ÷ ፲፱ አንተ ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ በኤፍሬም ፡ እጅ ፡ ያለውን ፡ የዮሴፍን ፡ በትር ፡ ባልንጀሮቹንም ፡ የእስራኤ ልን ፡ ነገዶች ፡ እወስዳለሁ ÷ ከእርሱም ፡ ከይ ሁዳ ፡ በትር ፡ ጋር ፡ አጋጥማቸዋለሁ ፡ አንድ ፡ በትርም ፡ አደርጋቸዋለሁ ÷ በእጄም ፡ ውስጥ ፡ ፳ አንድ ፡ ይሆናሉ ፡ በላቸው ። የምትጽፍባቸ ውም ፡ በትሮች ፡ በዓይናቸው ፡ ፊት ፡ በእጅህ ፡ ውስጥ ፡ ይሆናሉ ። ፳፩ አንተም ፡ እንዲህ ፡ ትላቸ ዋለህ ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ከሄ ዱባቸው ፡ ከአሕዛብ ፡ መካከል ፡ እወስዳለሁ ፡ ከስፍራም ፡ ሁሉ ፡ እሰበስባቸዋለሁ ፡ ወደ ፡ ገዛ ፡ ፳፪ ምድራቸውም ፡ አመጣቸዋለሁ ፤ በምድርም ፡ ላይ ፡ በእስራኤል ፡ ተራሮች ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ሕዝብ ፡ አደርጋቸዋለሁ ÷ አንድ ፡ ንጉሥም ፡ በሁላቸው ፡ ላይ ፡ ይነግሣል ፤ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ሁለት ፡ ሕዝብ ፡ አይሆኑም ÷ ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ ሁለት ፡ መንግሥቶች ፡ ሆነው ፡ አይለዩም ። ፳፫ ከዚያ ፡ ወዲያም ፡ በጣዖቶቻቸውና ፡ በርኵሰታ ቸው ፡ በመተላለፋቸውም ፡ ሁሉ ፡ አይረከሱም ÷ ኃጢአትም ፡ ከሠሩባት ፡ ዓመፅ ፡ ሁሉ ፡ አድና ቸዋለሁ ፡ አነጻቸውማለሁ ፤ ሕዝብም ፡ ይሆኑ ኛል ፡ እኔም ፡ አምላክ ፡ እሆናቸዋለሁ ።

፳፬ ባሪያዬም ፡ ዳዊት ፡ ንጉሥ ፡ ይሆናቸዋል ፤ ለሁሉም ፡ አንድ ፡ እረኛ ፡ ይሆንላቸዋል ፤ በፍር ዴም ፡ ይሄዳሉ ፡ ትእዛዜንም ፡ ይጠብቃሉ ፡ ያደ ርጓትማል ። ፳፭ አባቶቻችሁም ፡ በኖሩባት ፡ ለባ ሪያዬ ፡ ለያዕቆብ ፡ በሰጠኋት ፡ ምድር ፡ ይኖራሉ ፤ እነርሱና ፡ ልጆቻቸው ፡ የልጅ ፡ ልጆቻቸውም ፡ ለዘላለም ፡ ይኖሩባታል ፤ ባሪያዬም ፡ ዳዊት ፡ ለዘላለም ፡ አለቃ ፡ ይሆናቸዋል ። ፳፮ የሰላምም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ አደርጋለሁ ÷ የዘላለምም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ይሆንላቸዋል ፤ እኔም ፡ እባርካቸዋለሁ ፡ አበዛቸውማለሁ ፡ መቅ ደሴንም ፡ ለዘላለም ፡ በመካከላቸው ፡ አኖራለሁ ። ፳፯ ማደሪያዬም ፡ በላያቸው ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፤ እኔም ፡ አምላክ ፡ እሆናቸዋለሁ ፡ እነርሱም ፡ ሕዝብ ፡ ይሆኑኛል ። ፳፰ መቅደሴም ፡ ለዘላለም ፡ በመካከ ላቸው ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ÷ እኔ ፡ እስራኤልን ፡ የም ቀድሰው ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ አሕ ዛብ ፡ ያውቃሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፰ ።

፩ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን ፪ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ፊት ህን ፡ በጎግ ፡ ላይና ፡ በማጎግ ፡ ምድር ፡ ላይ ÷ በሞ ሳሕና ፡ በቶቤል ፡ ዋነኛ ፡ አለቃ ፡ ላይ ፡ አቅና በት ÷ ትንቢትም ፡ ተናገርበት ÷ ፫ እንዲህም ፡ በል ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የሞሳሕና ፡ የቶቤል ፡ ዋነኛ ፡ አለቃ ፡ ጎግ ፡ ሆይ ÷ እነሆ ÷ እኔ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ነኝ ። ፬ እመልስህማ ለሁ ፡ በመንጋጋህም ፡ ልጓም ፡ አገባብሃለሁ ÷ አንተንና ፡ ሠራዊትህንም ፡ ሁሉ ÷ ፈረሶችንና ፡ ፈረሰኞችን ፡ የጦር ፡ ልብስ ፡ የለበሱትን ፡ ሁሉ ÷ ጋሻና ፡ ራስ ፡ ቍርን ፡ ሰይፍንም ፡ የያዙትን ፡ ሁሉ ÷ ታላቁን ፡ ወገን ፡ አወጣለሁ ÷ ፭ ፋርስንና ፡ ኢትዮጵያን ፡ ፉጥንም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ጋሻና ፡ የራስ ፡ ቍርን ፡ የለበሱትን ፡ ሁሉ ÷ ፮ ጋሜርንና ፡ ጭፍሮቹን ፡ ሁሉ ÷ በሰሜን ፡ ዳርቻም ፡ ያለ ውን ፡ የቴርጋማን ፡ ቤትና ፡ ጭፍሮቹን ፡ ሁሉ ÷ ብዙዎችንም ፡ ሕዝቦች ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አወጣ ለሁ ።

፯ አንተና ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ የተሰበሰቡ ፡ ወገኖ ችህ ፡ ሁሉ ፡ ተዘጋጁ ÷ አንተም ፡ ራስህን ፡ አዘ ጋጅተህ ፡ አለቃ ፡ ሁናቸው ። ፰ ከብዙ ፡ ዘመንም ፡ በኋላ ፡ ትፈለጋለህ ፤ በኋለኛውም ፡ ዘመን ÷ የዘ ላለም ፡ ባድማ ፡ በነበሩ ፡ በእስራኤል ፡ ተራሮች ፡ ላይ ፡ ከብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ውስጥ ፡ ወደ ፡ ተሰበሰ በች ÷ ከሰይፍ ፡ ወደ ፡ ተመለሰች ፡ ምድር ፡ ትገባለህ ፤ እርስዋም ፡ ከሕዝብ ፡ ውስጥ ፡ ወጥ ታለች ፡ ሁሉም ፡ ሳይፈሩ ፡ ይቀመጡባታል ። ፱ አንተም ፡ ትወጣለህ ÷ እንደ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስም ፡ ትመጣለህ ፤ አንተና ፡ ጭፍሮችህ ፡ ሁሉ ፡ ከአን ተም ፡ ጋር ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ምድርን ፡ እንደ ፡ ደመና ፡ ትሸፍናላችሁ ።

፲ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በዚያ ፡ ቀን ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ልብህ ፡ ይገባል ÷ ክፉ ፡ አሳብንም ፡ ታስባለህ ÷ ፲፩ እንዲህም ፡ ትላ ለህ ፡— ቅጥር ፡ ወደሌላቸው ፡ መንደሮች ፡ እወ ጣለሁ ፤ ተዘልለው ፡ ወደሚኖሩ ÷ ሁላቸው ፡ ሳይፈሩ ፡ ያለ ፡ ቅጥርና ፡ ያለ ፡ መወርወሪያ ፡ ያለ ፡ መዝጊያም ፡ ወደሚቀመጡ ፡ እገባለሁ ፤ ፲፪ ምርኮን ፡ ትማርክ ፡ ዘንድ ፡ ብዝበዛንም ፡ ትበዘብዝ ፡ ዘንድ ÷ ባድማም ፡ በነበሩ ፡ አሁንም ፡ ሰዎች ፡ በሚኖሩ ባቸው ፡ ስፍራዎች ፡ ላይ ÷ ከአሕዛብም ፡ በተሰበ ሰበ ÷ ከብትና ፡ ዕቃንም ፡ ባገኘ ÷ በምድርም ፡ መካከል ፡ በተቀመጠ ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ እጅህን ፡ ትዘረጋ ፡ ዘንድ ። ፲፫ ሳባና ፡ ድዳን ፡ የተርሴስም ፡ ነጋዴዎች ፡ መንደሮችዋም ፡ ሁሉ ፡— ምርኮን ፡ ትማርክ ፡ ዘንድ ፡ መጥተሃልን ? ብዝበዛንስ ፡ ትበዘብዝ ፡ ዘንድ ፡ ብርንና ፡ ወርቅንስ ፡ ትወ ስድ ፡ ዘንድ ፡ ከብትንና ፡ ዕቃንስ ፡ ትወስድ ፡ ዘንድ ፡ እጅግስ ፡ ብዙ ፡ ምርኮ ፡ ትማርክ ፡ ዘንድ ፡ ወገንህን ፡ ሰብስበሃልን ? ይሉሃል ።

፲፬ አንተ ÷ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ስለዚህ ፡ ትን ቢት ፡ ተናገር ፡ ጎግንም ፡ እንዲህ ፡ በለው ፡— ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በዚያ ፡ ቀን ፡ ሕዝቤ ፡ እስራኤል ፡ ሳይፈራ ፡ በተቀመጠ ፡ ጊዜ ፡ አንተ ፡ አታውቀውምን? ፲፭ አንተም ÷ ከአን ተም ፡ ጋር ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ሁላቸው ፡ በፈረሶች ፡

ላይ ፡ የተቀመጡ ፥ ታላቅ ፡ ወገንና ፡ ብርቱ ፡
ሠራዊት ፥ ከሰሜን ፡ ዳርቻ ፡ ከስፍራችሁ ፡ ትመ
፲፮ ጣላችሁ ። ምድርንም ፡ ትሸፍን ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡
ደመና ፡ በሕዝቤ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ትወጣ
ለህ ። በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ ይሆናል ፥ ጎግ ፡
ሆይ ፥ በዓይናቸው ፡ ፊት ፡ በተቀደስሁብህ ፡
ጊዜ ፡ አሕዛብ ፡ ያውቁኝ ፡ ዘንድ ፡ በምድሬ ፡
ላይ ፡ አመጣሃለሁ ።

፲፯ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በእ
ነርሱ ፡ ላይ ፡ እንደማመጣህ ፡ በዚያች ፡ ዘመን ፡
ብዙ ፡ ዓመት ፡ ትንቢት ፡ በተናገሩ ፡ በባሪያዎቼ ፡
በእስራኤል ፡ ነቢያቶች ፡ በቀደመው ፡ ዘመን ፡
፲፰ ስለ ፡ እርሱ ፡ የተናገርሁ ፡ አንተ ፡ ነህን? በዚያም ፡
ቀን ፡ ጎግ ፡ በእስራኤል ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ በመጣ ፡
ጊዜ ፡ መቅሠፍቴ ፡ በመዓቴ ፡ ይመጣል ፥
፲፱ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። በቅንዓቴና ፡
በመዓቴ ፡ እሳት ፡ ተናግሬአለሁ ፡— በእርግጥ ፡
በዚያ ፡ ቀን ፡ በእስራኤል ፡ ምድር ፡ ጽኑ ፡ መና
፳ ወጥ ፡ ይሆናል ፤ ከፊቴም ፡ የተነሣ ፡ የባሕር ፡
ዓሣዎችና ፡ የሰማይ ፡ ወፎች ፡ የምድረ ፡ በዳም ፡
አራዊት ፡ በምድርም ፡ ላይ ፡ የሚንቀሳቀሱ ፡
ተንቀሳቃሾች ፡ ሁሉ ፡ በምድርም ፡ ላይ ፡ የሚኖሩ ፡
ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይንቀጠቀጣሉ ፥ ተራሮችም ፡ ይገ
ለባበጣሉ ፡ ገደላገደሎችም ፡ ይወድቃሉ ፡ ቅጥ
፳፩ ርም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ይወድቃል ። በተራሮ
ቼም ፡ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ሰይፍን ፡ እጠራለሁ ፥
የሰውም ፡ ሁሉ ፡ ሰይፍ ፡ በወንድሙ ፡ ላይ ፡ ይሆ
፳፪ ናል ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። በቸነፈ
ርና ፡ በደም ፡ እፈርድበታለሁ ፤ ዶፍም ፡ የበረ
ዶም ፡ ድንጋይ ፡ እሳትና ፡ ድኝም ፡ በእርሱና ፡
በጭፍሮቹ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ባሉ ፡ በብዙ ፡
፳፫ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ አዘንባለሁ ። ታላቅ ፡ እሆናለሁ ፡
እቀደስማለሁ ፡ በብዙ ፡ አሕዛብም ፡ ዓይን ፡ የታ
ወቅሁ ፡ እሆናለሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡
እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፴፱ ።

፩ አንተም ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ በጎግ ፡ ላይ ፡ ትን
ቢትን ፡ ተናገር ፡ እንዲህም ፡ በል ፡— ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የሞሳሕና ፡ የቶ
ቤል ፡ ዋነኛ ፡ አለቃ ፡ ጎግ ፡ ሆይ ፥ እነሆ ፥ እኔ ፡
፪ በአንተ ፡ ላይ ፡ ነኝ ፤ እመልስሃለሁ ፥ እነዳህማ
ለሁ ፥ ከሰሜንም ፡ ዳርቻ ፡ እጐትትሃለሁ ፥ ወደ ፡
፫ እስራኤልም ፡ ተራሮች ፡ አመጣሃለሁ ። ከግራ ፡
እጅህም ፡ ቀስትህን ፡ አስጥልሃለሁ ፥ ከቀኝ ፡
፬ እጅህም ፡ ፍላጾችህን ፡ አስረግፍሃለሁ ። አን
ተና ፡ ጭፍሮችህ ፡ ሁሉ ፡ ከአንተም ፡ ጋር ፡
ያሉ ፡ ሕዝብ ፡ በእስራኤል ፡ ተራሮች ፡ ላይ ፡
ትወድቃላችሁ ፤ ለሚናጠቁ ፡ ወፎች ፡ ሁሉና ፡
ለምድር ፡ አራዊትም ፡ መብል ፡ አድርጌ ፡ እሰጥ
፭ ሃለሁ ። አንተ ፡ በምድር ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ ትወ
ድቃለህ ፤ እኔ ፡ ተናግሬአለሁና ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡
፮ እግዚአብሔር ። በማጎግም ፡ ላይ ፡ ሳይፈሩም ፡
በደሴቶች ፡ በሚቀመጡ ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ እሰ
ድዳለሁ ፤ እኔም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡
፯ ያውቃሉ ። ቅዱሱም ፡ ስሜ ፡ በሕዝቤ ፡ በእስ
ራኤል ፡ መካከል ፡ ይታወቅ ፡ ዘንድ ፡ አደርጋ
ለሁ ፥ ቅዱሱንም ፡ ስሜን ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
አላስረክስም ፤ አሕዛብም ፡ እግዚአብሔር ፥ የእስ
ራኤል ፡ ቅዱስ ፥ እኔ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ያውቃሉ ።
፰ እነሆ ፥ ይመጣል ፡ ይሆንማል ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡
፱ እግዚአብሔር ፤ ያልሁት ፡ ቀን ፡ ይህ ፡ ነው ። በእ
ስራኤልም ፡ ከተሞች ፡ የሚኖሩ ፡ ይወጣሉ ፥
የጦር ፡ መሣሪያዎችንም ፡ በእሳት ፡ ያቃጥላሉ ፤
አላባሽ ፡ ጋሻንና ፡ ጋሻን ፥ ቀስትንና ፡ ፍላጻዎ
ችን ፥ ጎመድንና ፡ ጦርንም ፡ ያቃጥላሉ ፤ ሰባት ፡
፲ ዓመት ፡ በእሳት ፡ ያቃጥሉአቸዋል ። በጦር ፡
መሣሪያው ፡ እሳትን ፡ ያነድዳሉ ፡ እንጂ ፡ እን
ጨትን ፡ ከምድረ ፡ በዳ ፡ አይወስዱም ፡ ከዱርም ፡
አይቈርጡም ፤ የገፈፉአቸውንም ፡ ይገፍፋሉ ፡
የበዘበዙአቸውንም ፡ ይበዝብዛሉ ፥ ይላል ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፲፩ በዚያም ፡ ቀን ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ በባ
ሕር ፡ ምሥራቅ ፡ የሚያልፉበትን ፡ ሸለቆ ፡ የመ
ቃብርን ፡ ስፍራ ፡ ለጎግ ፡ እሰጣለሁ ፥ የሚያል
ፉትንም ፡ ይከለክላል ፤ በዚያም ፡ ጎግንና ፡ ብዛ
ቱን ፡ ሁሉ ፡ ይቀብራሉ ፤ የሸለቆውንም ፡ ስም ፡
፲፪ ሐሞንጎግ ፡ ብለው ፡ ይጠሩታል ። ምድሩንም ፡
ያጸዱ ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሰዎች ፡ ሰባት ፡
፲፫ ወር ፡ ይቀብሩአቸዋል ፥ የምድርም ፡ ሕዝብ ፡
ሁሉ ፡ ይቀብሩአቸዋል ፥ በተመሰገንሁበትም ፡
ቀን ፡ ለክብር ፡ ይሆንላችኋል ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡
፲፬ እግዚአብሔር ። ምድርንም ፡ ለማጽዳት ፡ በም
ድሩ ፡ ላይ ፡ ወድቀው ፡ የቀሩትን ፡ የሚቀብሩ ፥
ዘወትር ፡ በምድሩ ፡ ላይ ፡ የሚዞሩትን ፡ ሰዎች ፡
ይቀጥራሉ ፤ ከሰባት ፡ ወርም ፡ በኋላ ፡ ይመረም
፲፭ ራሉ ። በምድርም ፡ የሚዞሩት ፡ ያልፋሉ ፤ የሰ
ውንም ፡ አጥንት ፡ ቢያዩ ፥ ቀባሪዎች ፡ በሐሞን
ጎግ ፡ ሸለቆ ፡ እስኪቀብሩት ፡ ድረስ ፡ ምልክት ፡
፲፮ ያኖሩበታል ። ደግሞም ፡ የከተማይቱ ፡ ስም ፡
ሐሞና ፡ ይባላል ። እንዲሁ ፡ ምድሪቱን ፡ ያጸ
ዳሉ ።

፲፯ አንተም ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ጌታ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ለወፎች ፡ ሁሉና ፡
ለምድር ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ በላቸው ፡—
ኑ ፥ ተከማቹ ፥ ሥጋንም ፡ ትበሉ ፡ ዘንድ ፡ ደም
ንም ፡ ትጠጡ ፡ ዘንድ ፡ በእስራኤል ፡ ተራሮች ፡
ላይ ፡ ወደማርድላችሁ ፡ መሥዋዕት ፥ እርሱም ፡
ታላቅ ፡ መሥዋዕት ፥ ከየስፍራው ፡ ሁሉ ፡ ተሰ
፲፰ ብሰቡ ። የኃያላኑን ፡ ሥጋ ፡ ትበላላችሁ ፡ የም
ድርንም ፡ አለቆች ፥ የአውራ ፡ በጎችንና ፡ የጠ
ቦቶችን ፥ የፍየሎችንና ፡ የወይፈኖችን ፥ የባ
ሳንን ፡ ፍሪዳዎች ፡ ሁሉ ፥ ደም ፡ ትጠጣላችሁ ።
፲፱ እኔም ፡ ከማርድላችሁ ፡ መሥዋዕት ፡ እስክት
ጠግቡ ፡ ድረስ ፡ ጮማ ፡ ትበላላችሁ ፡ እስክትሰ
፳ ክሩም ፡ ድረስ ፡ ደም ፡ ትጠጣላችሁ ። በሰደቃ
ዬም ፡ ከፈረሶችና ፡ ከፈረሰኞች ፥ ከኃያላንና ፡
ከሰልፈኞች ፡ ሁሉ ፡ ትጠግባላችሁ ፥ ይላል ፡

ጌታ፡እግዚአብሔር።

፳፩፤ ክብሬንም፡በአሕዛብ፡መካከል፡አኖራለሁ፡ አሕዛብም፡ሁሉ፡ያደረግሁትን፡ፍርዴን÷ ፳፪፤ በላያቸውም፡ያኖርኋትን፡እጄን፡ያያሉ። ከእንግዲህም፡ወዲያ፡የእስራኤል፡ቤት፡እኔ፡ እግዚአብሔር፡አምላካቸው፡እንደ፡ሆንሁ፡ ፳፫፤ ያውቃሉ። አሕዛብም፡የእስራኤል፡ቤት፡ በኃጢአታቸው፡ምክንያት፡እንደ፡ተማረኩ፡ ያውቃሉ፤ ስለ፡በደሉኝ፡እኔም፡ፊቴን፡ከእነርሱ፡ስለ፡ሸሸግሁ÷በጠላቶቻቸው፡እጅ፡ አሳልፌ፡ሰጠኋቸው÷እነርሱም፡ሁሉ፡በሰ ፳፬፤ ይፍ፡ወደቁ። እንደ፡ርኵሰታቸውም፡እንደ፡ መተላለፋቸውም፡መጠን፡አደረግሁባቸው፤ ፊቴንም፡ከእነርሱ፡ሸሸግሁ።

፳፭፤ ስለዚህ፡ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ ይላል፡— አሁን፡የያዕቆብን፡ምርኮ፡እመልሳለሁ፡ለእስራኤልም፡ቤት፡ሁሉ፡እራራለሁ÷ ፳፮፤፳፯፤ ስለ፡ቅዱስ፡ስሜም፡እቀናለሁ። ማንም፡ሳያስፈራቸው፡በምድራቸው፡ተዘልለው፡በተቀመጡ፡ጊዜ፡ከአሕዛብም፡ዘንድ፡በመለስኋቸው፡ጊዜ፡ከጠላቶቻቸውም፡ምድር፡በሰበሰብኋቸው፡ጊዜ፡በብዙ፡አሕዛብም፡ፊት፡በተቀደስሁባቸው፡ጊዜ÷እፍረታቸውንና፡የበደሉኝን፡በደላቸውን፡ሁሉ፡ይሸከማሉ። ፳፰፤ እኔም፡ወደ፡አሕዛብ፡አስማርኬአቸዋለሁና÷ ወደ፡ገዛ፡ምድራቸውም፡ሰብስቤአቸዋለሁና፡እኔ፡እግዚአብሔር፡አምላካቸው፡እንደ፡ ሆንሁ፡ያውቃሉ፤ በዚያም፡ከእነርሱ፡አንድ፡ ፳፱፤ ሰው፡ከእንግዲህ፡ወዲያ፡አልተውም÷ፊቴንም፡ከእነርሱ፡ከእንግዲህ፡ወዲህ፡አልሸሽግም፤መንፈሴን፡በእስራኤል፡ቤት፡ላይ፡አፍስሻለሁና÷ይላል፡ጌታ፡እግዚአብሔር።

ምዕራፍ፡፵።

፩፤ በተማረክን፡በሀያ፡አምስተኛው፡ዓመት፡ በዓመቱ፡መጀመሪያ፡ከወሩ፡በአሥረኛው፡ ቀን÷ከተማይቱ፡ከተመታች፡በኋላ፡በአሥራ፡ አራተኛው፡ዓመት÷በዚያው፡ቀን፡የእግዚአብሔር፡እጅ፡በእኔ፡ላይ፡ነበረ፡እርሱም፡ ፪፤ ወደዚያ፡ወሰደኝ። በእግዚአብሔር፡ራእይ፡ ወደ፡እስራኤል፡ምድር፡አመጣኝ፡እጅግም፡በረዘመ፡ተራራ፡ላይ፡አኖረኝ÷ በዚያም፡ላይ፡በደቡብ፡ወገን፡እንደ፡ ፫፤ ከተማ፡ሆኖ፡የተሠራ፡ነገር፡ነበረ። ወደዚያም፡አመጣኝ÷እነሆም÷መልኩ፡እንደ፡ናስ፡መልክ፡የመሰለ፡አንድ፡ሰው፡በዚያ፡ ነበረ÷በእጁም፡የተልባ፡እግር፡ገመድና፡ የመለኪያ፡ዘንግ፡ነበረ፤ እርሱም፡በበሩ፡ ፬፤ አጠገብ፡ቆሞ፡ነበር። ሰውዬውም፡— የሰው፡ ልጅ፡ሆይ÷ይህን፡አሳይህ፡ዘንድ፡አንተ፡ ወደዚህ፡ተመርተሃልና፡በዓይንህ፡እይ፡በጆሮህም፡ስማ፡በማሳይህም፡ሁሉ፡ላይ፡ልብህን፡አድርግ፤ የምታየውንም፡ሁሉ፡ለእስራኤል፡ቤት፡ንገር፡አለኝ።

፭፤ እነሆም÷በቤቱ፡ውጭ፡በዙሪያው፡ቅጥር፡ ነበረ÷በሰውዬውም፡እጅ፡የክንዱ፡ልክ፡አንድ፡ ክንድ፡ከጋት፡የሆነ፡ስድስት፡ክንድ፡ያለበት፡ የመለኪያ፡ዘንግ፡ነበረ፤ የቅጥሩንም፡ስፋት፡ አንድ፡ዘንግ፡ቁመቱንም፡አንድ፡ዘንግ፡አድርጎ፡ለካ። ፮፤ ወደ፡ምሥራቅ፡ወደሚመለከተውም፡በር፡መጣ፡በደረጃዎቹም፡ላይ፡ወጣ÷ በበሩ፡በኩል፡ያለውንም፡የመድረኩን፡ወለል፡ ወርዱን፡አንድ፡ዘንግ፡አድርጎ፡ለካ። ፯፤ የዘበኛውም፡ጓዳ፡ሁሉ፡ርዝመቱ፡አንድ፡ዘንግ÷ ወርዱም፡አንድ፡ዘንግ፡ነበረ፤ በዘበኛውም፡ ጓዳዎች፡መካከል፡አምስት፡ክንድ፡ነበረ፤ በበሩም፡ደጀ፡ሰላም፡በስተ፡ውስጥ፡በኩል፡ የሚገኝ፡የበሩ፡የመድረክ፡ወለል፡አንድ፡ ዘንግ፡ነበረ። ፰፤ በስተ፡ውስጥም፡ያለውን፡ የበሩን፡ደጀ፡ሰላም፡አንድ፡ዘንግ፡አድርጎ፡ ለካ። ፱፤ የበሩንም፡ደጀ፡ሰላም፡ስምንት፡ክንድ÷ የግንቡንም፡አዕማድ፡ወርድ፡ሁለት፡ክንድ፡ አድርጎ፡ለካ፤ የበሩም፡ደጀ፡ሰላም፡በስተ፡ ውስጥ፡ነበረ። ፲፤ የምሥራቁም፡በር፡የዘበኛ፡ ጓዳዎች፡በዚህ፡በኩል፡ሦስት፡በዚያም፡ በኩል፡ሦስት፡ነበሩ÷ለሦስቱም፡አንድ፡ ልክ፡ነበረ፤ የግንቡም፡አዕማድ፡ወርድ፡በዚህ፡ በኩልና፡በዚያ፡በኩል፡አንድ፡ልክ፡ነበረ። ፲፩፤ የበሩንም፡መግቢያ፡ወርድ፡አሥር፡ክንድ፡ የበሩንም፡ርዝመት፡አሥራ፡ሦስት፡ክንድ፡ አድርጎ፡ለካ። ፲፪፤ በዘበኛ፡ጓዳዎችም፡ፊት፡ በዚህ፡በኩል፡አንድ፡ክንድ፡በዚያም፡ በኩል፡አንድ፡ክንድ፡የሆነ፡ዳርቻ፡ነበረ፤ የዘበኛ፡ጓዳዎቹም፡በዚህ፡በኩል፡ስድስት፡ክንድ፡ በዚያም፡በኩል፡ስድስት፡ክንድ፡ነበሩ። ፲፫፤ ከአንዱም፡የዘበኛ፡ጓዳ፡ደርብ፡ጀምሮ፡እስከ፡ ሌላው፡ደርብ፡ድረስ፡የበሩን፡ወርድ፡ሀያ፡ አምስት፡ክንድ፡አድርጎ፡ለካ፤ መዝጊያውና፡ ፲፬፤ መዝጊያውም፡ትይዩ፡ነበረ። ደጀ፡ሰላሙንም፡ሀያ፡ክንድ፡አድርጎ፡ለካ፤ በበሩም፡ ፲፭፤ ደጀ፡ሰላም፡ዙሪያ፡አደባባይ፡ነበረ። ከበሩም፡ መግቢያ፡ፊት፡ጀምሮ፡እስከ፡ውስጠኛው፡ የበሩ፡ደጀ፡ሰላም፡መጨረሻ፡ድረስ፡አምሳ፡ ፲፮፤ ክንድ፡ነበረ። በዘበኛ፡ጓዳዎቹም፡በበሩ፡ ውስጥ፡በዙሪያው፡በነበሩትም፡በግንቡ፡አዕማድ፡የዓይነ፡ርግብ፡መስኮቶች፡ነበሩባቸው፤ ደግሞም፡በደጀ፡ሰላሙ፡ውስጥ፡በዙሪያው፡ መስኮቶች፡ነበሩ፤ በግንቡም፡አዕማድ፡ሁሉ፡ ላይ፡የዘንባባ፡ዛፍ፡ተቀርጾባቸው፡ነበር።

፲፯፤ ወደ፡ውጭውም፡አደባባይ፡አመጣኝ÷ እነሆም÷በአደባባዩ፡ዙሪያ፡የተሠሩ፡ዕቃ፡ ቤቶችና፡ወለል፡ነበሩ፤ በወለሉም፡ላይ፡ ፲፰፤ ሠላሳ፡ዕቃ፡ቤቶች፡ነበሩ። ወለሉም፡በበሮች፡አጠገብ፡ነበረ፡ይህም፡ታችኛው፡ወለል፡ ፲፱፤ እንደ፡በሮቹ፡ርዝመት፡መጠን፡ነበረ። ከታችኛውም፡በር፡ፊት፡ጀምሮ፡እስከ፡ውስጠኛው፡አደባባይ፡ፊት፡ድረስ፡ወርዱን፡አንድ፡ መቶ፡ክንድ፡አድርጎ፡ለካ።

፳፤ ወደ ፡ ሰሜንም ፡ መራኝ ፥ እነሆም ፥ በውጭው ፡ አደባባይ ፡ ያለ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ የሚመለከት ፡ በር ፡ ነበረ ፤ ርዝመቱንና ፡ ወርዱንም ፡ ለካ ። ፳፩፤ የዘበኛ ፡ ጓዳዎቹም ፡ በዚህ ፡ በኩል ፡ ሦስት ፡ በዚያም ፡ በኩል ፡ ሦስት ፡ ነበሩ ፤ የግንቡ ፡ አዕማድና ፡ መዛነቢያዎቹም ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ በር ፡ ልክ ፡ ነበሩ ፤ ርዝመቱ ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፳፪፤ መስኮቶቹም ፡ መዛነቢያዎቹም ፡ የዘንባባ ፡ ዛፎቹም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ እንደሚመለከተው ፡ በር ፡ ልክ ፡ ነበሩ ። ወደ ፡ እርሱም ፡ የሚያደርሱ ፡ ሰባት ፡ ደረጃዎች ፡ ነበሩ ፡ መዛነቢያዎቹም ፡ በፊቱ ፡ ነበሩ ። ፳፫፤ በውስጠኛውም ፡ አደባባይ ፡ በሰሜኑና ፡ በምሥራቁ ፡ በኩል ፡ በሌላው ፡ በር ፡ አንጻር ፡ በር ፡ ነበረ ፤ ከበርም ፡ ወደ ፡ በር ፡ አንድ ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ።

፳፬፤ ወደ ፡ ደቡብም ፡ መራኝ ፥ እነሆም ፥ ወደ ፡ ደቡብ ፡ የሚመለከት ፡ በር ፡ ነበረ ፤ የግንቡን ፡ አዕማድና ፡ መዛነቢያዎቹንም ፡ እንደዚያው ፡ መጠን ፡ አድርጎ ፡ ለካ ። ፳፭፤ በእርሱና ፡ በመዛነቢያዎቹም ፡ ዙሪያ ፡ እንደ ፡ እነዚያ ፡ መስኮቶች ፡ የሚመስሉ ፡ መስኮቶች ፡ ነበሩ ፤ ርዝመቱ ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፳፮፤ ወደ ፡ እርሱም ፡ የሚያደርሱ ፡ ሰባት ፡ ደረጃዎች ፡ ነበሩ ፥ መዛነቢያዎቹም ፡ በፊቱ ፡ ነበሩ ፤ በግንቡም ፡ አዕማድ ፡ ላይ ፡ አንዱ ፡ በዚህ ፡ አንዱም ፡ በዚያ ፡ ወገን ፡ ሆኖ ፡ የዘንባባ ፡ ዛፍ ፡ ተቀርጾባቸው ፡ ነበር ። ፳፯፤ በውስጠኛውም ፡ አደባባይ ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ በር ፡ ነበረ ፤ ከበር ፡ እስከ ፡ በር ፡ ድረስ ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ።

፳፰፤ በደቡብም ፡ በር ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ውስጠኛው ፡ አደባባይ ፡ አገባኝ ፤ እንደዚያውም ፡ መጠን ፡ አድርጎ ፡ የደቡብን ፡ በር ፡ ለካ ፤ ፳፱፤ እንደዚያውም ፡ መጠን ፡ አድርጎ ፡ የዘበኛ ፡ ጓዳዎቹንና ፡ የግንቡን ፡ አዕማድ ፡ መዛነቢያዎቹንም ፡ ለካ ፤ በእርሱና ፡ በመዛነቢያዎቹም ፡ ዙሪያ ፡ መስኮቶች ፡ ነበሩ ፤ ርዝመቱ ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፴፤ በዙሪያውም ፡ ደጀ ፡ ሰላሞች ፡ ነበሩ ፤ ርዝመታቸውም ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ወርዳቸውም ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፴፩፤ መዛነቢያዎቹም ፡ ወደ ፡ ውጭው ፡ አደባባይ ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ፤ በግንቡም ፡ አዕማድ ፡ ላይ ፡ የዘንባባ ፡ ዛፍ ፡ ተቀርጾ ፡ ነበር ፤ ወደ ፡ እርሱም ፡ የሚያደርሱ ፡ ስምንት ፡ ደረጃዎች ፡ ነበሩ ።

፴፪፤ በውስጠኛውም ፡ አደባባይ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ አገባኝ ፥ እንደዚያውም ፡ መጠን ፡ በሩን ፡ ለካ ፤ ፴፫፤ እንደዚያውም ፡ መጠን ፡ የዘበኛ ፡ ጓዳዎቹንና ፡ የግንቡን ፡ አዕማድ ፡ መዛነቢያዎቹንም ፡ ለካ ፤ በእርሱና ፡ በመዛነቢያዎቹም ፡ ዙሪያ ፡ መስኮቶች ፡ ነበሩ ፥ ርዝመቱም ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፴፬፤ መዛነቢያዎቹም ፡ በስተ ፡ ውጭ ፡ ወዳለው ፡ አደባባይ ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ፤ በግንቡም ፡ አዕማድ ፡ ላይ ፡ በዚህና ፡ በዚያ ፡ ወገን ፡ የዘንባባ ፡ ዛፍ ፡ ተቀርጾ ፡ ነበር ፤ ወደ ፡ እርሱም ፡ የሚያደርሱ ፡ ስምንት ፡ ደረጃዎች ፡ ነበሩት ።

፴፭፤ በሰሜንም ፡ ወዳለው ፡ በር ፡ አመጣኝ ፥ ፴፮፤ እንደዚያውም ፡ መጠን ፡ ለካው ፡ የዘበኛ ፡ ጓዳዎቹንና ፡ የግንቡን ፡ አዕማድ ፡ መዛነቢያዎቹንም ፡ ለካ ፤ በዙሪያውም ፡ መስኮቶች ፡ ነበሩበት ፥ ርዝመቱም ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፴፯፤ የግንቡም ፡ አዕማድ ፡ ወደ ፡ ውጭው ፡ አደባባይ ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ፤ በግንቡም ፡ አዕማድ ፡ ላይ ፡ በዚህና ፡ በዚያ ፡ ወገን ፡ የዘንባባ ፡ ዛፍ ፡ ተቀርጾ ፡ ነበር ፤ ወደ ፡ እርሱም ፡ የሚያደርሱ ፡ ስምንት ፡ ደረጃዎች ፡ ነበሩት ።

፴፰፤ በበሮቹም ፡ በግንብ ፡ አዕማድ ፡ አጠገብ ፡ ዕቃ ፡ ቤቱና ፡ መዝጊያው ፡ ነበሩ ፤ በዚያ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ያጥቡ ፡ ነበር ። ፴፱፤ የሚቃጠለውንም ፡ መሥዋዕት ፡ የኃጢአቱንና ፡ የበደሉንም ፡ መሥዋዕት ፡ ያርዱባቸው ፡ ዘንድ ፥ በበሩ ፡ ደጀ ፡ ሰላም ፡ በዚህ ፡ ወገን ፡ ሁለት ፡ ገበታዎች ፥ በዚያም ፡ ወገን ፡ ሁለት ፡ ገበታዎች ፡ ነበሩ ። ፵፤ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ባለው ፡ በር ፡ በስተ ፡ ውጭው ፥ በመወጣጫው ፡ ደረጃዎች ፡ አጠገብ ፥ በአንዱ ፡ ወገን ፡ ሁለት ፡ ገበታዎች ፡ ነበሩ ፥ በሌላውም ፡ ወገን ፡ በበሩ ፡ ደጀ ፡ ሰላም ፡ በኩል ፡ ሁለት ፡ ገበታዎች ፡ ነበሩ ። ፵፩፤ በበሩ ፡ አጠገብ ፡ በዚህ ፡ ወገን ፡ አራት ፡ ገበታዎች ፡ በዚያም ፡ ወገን ፡ አራት ፡ ገበታዎች ፡ ነበሩ ፤ መሥዋዕት ፡ የሚያርዱባቸው ፡ ገበታዎች ፡ ስምንት ፡ ነበሩ ። ፵፪፤ ስለሚቃጠለውም ፡ መሥዋዕት ፡ ርዝመታቸው ፡ ክንድ ፡ ተኩል ፡ ወርዳቸውም ፡ ክንድ ፡ ተኩል ፡ ቁመታቸውም ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ የሆኑ ፥ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ ሌላ ፡ መሥዋዕቱን ፡ የሚያርዱበትን ፡ ዕቃ ፡ ያኖሩባቸው ፡ ዘንድ ፥ ከተጠረበ ፡ ድንጋይ ፡ የተሠሩ ፡ አራት ፡ ገበታዎች ፡ ነበሩ ። ፵፫፤ በዙሪያውም ፡ አንድ ፡ ጋት ፡ የሆነ ፡ ክፈፍ ፡ ወደ ፡ ውስጥ ፡ ተቀልብሶ ፡ ነበር ፤ በገበታዎቹም ፡ ላይ ፡ የቍርባኑ ፡ ሥጋ ፡ ነበረባቸው ።

፵፬፤ ወደ ፡ ውስጠኛውም ፡ አደባባይ ፡ አገባኝ ፥ እነሆም ፥ ሁለት ፡ ቤቶች ፡ ነበሩ ፤ አንዱ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ በሚመለከት ፡ በር ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ፥ መግቢያውም ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ ይመለከት ፡ ነበር ፤ ሌላውም ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ በሚመለከተው ፡ በር ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ፥ መግቢያውም ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ይመለከት ፡ ነበር ። ፵፭፤ ሰውዬውም ፡— ይህ ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ የሚመለከት ፡ ቤት ፡ ለማገልገል ፡ ለሚተጉ ፡ ካህናት ፡ ነው ። ፵፮፤ ወደ ፡ ሰሜንም ፡ የሚመለከተው ፡ ቤት ፡ መሠዊያውን ፡ ለማገልገል ፡ ለሚተጉ ፡ ካህናት ፡ ነው ፤ እነዚህ ፡ ከሌዊ ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ያገለግሉት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚቀርቡ ፡ የሳዶቅ ፡ ልጆች ፡ ናቸው ፡ አለኝ ። ፵፯፤ አደባባዩንም ፡ በአራት ፡ ማዕዘኑ ፡ ርዝመቱን ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ ወርዱንም ፡

መቶ ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ፤ መሠዊያውም ፡ በቤቱ ፡ ፊት ፡ ነበረ ።

፵፰ ወደ ፡ ቤቱም ፡ ደጀ ፡ ሰላም ፡ አመጣኝ ፥ የደጀ ፡ ሰላሙንም ፡ የግንብ ፡ አዕማድ ፡ ወርድ ፡ በዚህ ፡ ወገን ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ በዚያም ፡ ወገን ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ፤ የበሩም ፡ ወርድ ፡ አሥራ ፡ አራት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ በበሩም ፡ በዚህ ፡ ወገንና ፡ በዚያ ፡ ወገን ፡ የነበሩት ፡ ግንቦች ፡ ሦስት ፡ ሦስት ፡ ክንድ ፡ ነበሩ ። ፵፱ የደጀ ፡ ሰላሙም ፡ ርዝመት ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ ወደ ፡ እርሱም ፡ የሚያደርሱ ፡ አሥር ፡ ደረጃዎች ፡ ነበሩ ፤ አንድ ፡ በዚህ ፡ ወገን ፡ አንድም ፡ በዚያ ፡ ወገን ፡ ሆነው ፡ በመቃኖቹ ፡ አጠገብ ፡ የግንብ ፡ አዕማድ ፡ ነበሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፩ ።

፩ ወደ ፡ መቅደሱም ፡ አገባኝ ፥ የግንቡንም ፡ አዕማድ ፡ ወርድ ፡ በዚህ ፡ ወገን ፡ ስድስት ፡ ክንድ ፡ በዚያም ፡ ወገን ፡ ስድስት ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ። ፪ የመግቢያውም ፡ ወርድ ፡ አሥር ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ የመግቢያውም ፡ መቃኖች ፡ በዚህ ፡ ወገን ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ በዚያም ፡ ወገን ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበሩ ፤ ርዝመቱንም ፡ አርባ ፡ ክንድ ፡ ወርዱንም ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ። ፫ ወደ ፡ ውስጥም ፡ ገባ ፥ የመግቢያውንም ፡ የግንብ ፡ አዕማድ ፡ ወርድ ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ፤ የመግቢያውም ፡ ወርድ ፡ ስድስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፥ የመግቢያውም ፡ ግንብ ፡ ወርድ ፡ በዚህ ፡ ወገን ፡ ሰባት ፡ ክንድ ፡ በዚያም ፡ ወገን ፡ ሰባት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፬ በመቅደሱም ፡ ፊት ፡ ርዝመቱን ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፡ ወርዱንም ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካና ፡— ይህ ፡ ቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፡ ነው ፡ አለኝ ።

፭ የመቅደሱንም ፡ ግንብ ፡ ስድስት ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፥ በመቅደሱም ፡ ዙሪያ ፡ ሁሉ ፡ ያሉትን ፡ የጓዳዎቹን ፡ ሁሉ ፡ ወርድ ፡ አራት ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ። ፮ ጓዳዎቹም ፡ አንዱ ፡ ከአንዱ ፡ በላይ ፡ በሦስት ፡ ደርብ ፡ ነበሩ ፥ በእያንዳንዱም ፡ ደርብ ፡ ሠላሳ ፡ ጓዳዎች ፡ ነበሩ ። በመቅደሱም ፡ ግንብ ፡ ዙሪያ ፡ ደገፋዎች ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ አረፍቶች ፡ ነበሩ ፥ በመቅደሱም ፡ ግንብ ፡ ውስጥ ፡ ደገፋዎች ፡ አልነበሩም ። ፯ በቤቱም ፡ ዙሪያ ፡ ባለ ፡ ግንብ ፡ ውስጥ ፡ በነበሩት ፡ አረፍቶች ፡ ምክንያት ፡ ላይኞቹ ፡ ጓዳዎች ፡ ከታችኞቹ ፡ ጓዳዎች ፡ ይበልጡ ፡ ነበር ፤ ከታችኛውም ፡ ደርብ ፡ ወደ ፡ መካከለኛው ፡ ከመካከለኛውም ፡ ደርብ ፡ ወደ ፡ ላይኛው ፡ የሚወጣበት ፡ ደረጃ ፡ ነበረ ። ፰ ለመቅደሱም ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ወለል ፡ በዙሪያው ፡ እንዳለው ፡ አየሁ ፤ የጓዳዎቹም ፡ መሠረት ፡ ቁመቱ ፡ ሙሉ ፡ ዘንግ ፡ የሚያህል ፡ ስድስት ፡ ትልቅ ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፱ የጓዳዎቹም ፡ የውጭው ፡ ግንብ ፡ ውፍረት ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ፤ በመቅደሱም ፡ ጓዳዎች ፡ አጠገብ ፡ የቀረ ፡ አንድ ፡ ባዶ ፡ ስፍራ ፡ ነበረ ። ፲ ፲፩ በዚህም ፡ በባዶው ፡ ስፍራ ፡ አንዱ ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ አንዱም ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ የጓዳዎች ፡ መግቢያ ፡ ነበረ ፤ የባዶውም ፡ ስፍራ ፡ ወርድ ፡ በዙሪያ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። በመቅደሱም ፡ ዙሪያ ፡ ወርዱ ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፡ ልዩ ፡ ስፍራ ፡ ነበረ ።

፲፪ በምዕራብም ፡ በኩል ፡ በልዩ ፡ ስፍራ ፡ አንጻር ፡ የነበረ ፡ ግቢ ፡ ስፋቱ ፡ ሰባ ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። በግቢውም ፡ ዙሪያ ፡ የነበረ ፡ ግንብ ፡ ውፍረቱ ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ ርዝመቱም ፡ ዘጠና ፡ ክንድ ፡ ነበረ ።

፲፫ የመቅደሱንም ፡ ርዝመት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፥ የልዩውን ፡ ስፍራና ፡ ግቢውን ፡ ከግንቡ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ። ፲፬ ደግሞም ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ የነበረውን ፡ የመቅደሱንና ፡ የልዩውን ፡ ስፍራ ፡ ወርድ ፡ አንድ ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ። ፲፭ ወደ ፡ ኋላውም ፡ ባለው ፡ በልዩ ፡ ስፍራ ፡ አንጻር ፡ የነበረውን ፡ የግቢውን ፡ ርዝመት ፡ በዚህና ፡ በዚያም ፡ ከነበሩት ፡ ከግንቦቹ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ።

፲፮ መድረኮቹ ፥ መቅደሱና ፡ በስተ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፡ ክፍል ፡ ደጀ ፡ ሰላሙም ፡ በእንጨት ፡ ተለብጠው ፡ ነበር ፥ በሦስቱም ፡ ዙሪያ ፡ የዓይነ ፡ ርግብ ፡ መስኮቶች ፡ ነበሩ ። መቅደሱም ፡ በመድረኩ ፡ አንጻር ፡ ከመሬት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ መስኮቶቹ ፡ ድረስ ፡ በእንጨት ፡ ተለብጦ ፡ ነበር ፤ መስኮቶቹም ፡ የዓይነ ፡ ርግብ ፡ ነበሩ ፤ ፲፯ በደጁም ፡ ላይ ፡ እስከ ፡ ውስጠኛው ፡ ክፍል ፡ ድረስ ፥ በውጭም ፡ ግንቡ ፡ ሁሉ ፡ ውስጡም ፡ ውጭውም ፡ ተለብጦ ፡ ነበር ። ፲፰ ኪሩቤልና ፡ የዘንባባው ፡ ዛፎች ፡ ተቀርጸውበት ፡ ነበር ፤ የዘንባባውም ፡ ዛፍ ፡ ከኪሩብና ፡ ከኪሩብ ፡ መካከል ፡ ነበረ ፤ ለእያንዳንዱም ፡ ኪሩብ ፡ ሁለት ፡ ፊት ፡ ነበረው ። ፲፱ በአንድ ፡ ወገን ፡ ወዳለው ፡ የዘንባባ ፡ ዛፍ ፡ የሰው ፡ ፊት ፡ ይመለከት ፡ ነበር ፥ በሌላውም ፡ ወገን ፡ ወዳለው ፡ የዘንባባ ፡ ዛፍ ፡ የአንበሳ ፡ ፊት ፡ ይመለከት ፡ ነበር ፤ በቤቱ ፡ ሁሉ ፡ ዙሪያ ፡ እንደዚህ ፡ ተደርጎ ፡ ነበር ። ፳ ከመሬት ፡ አንሥቶ ፡ እስከ ፡ ደጁ ፡ ራስ ፡ ድረስ ፡ ኪሩቤልና ፡ የዘንባባ ፡ ዛፎች ፡ ተቀርጸው ፡ ነበር ። የመቅደሱ ፡ ግንብ ፡ እንደዚህ ፡ ነበረ ።

፳፩ የመቅደሱ ፡ መቃኖችም ፡ አራት ፡ ማዕዘን ፡ ነበሩ ፥ የመቅደሱ ፡ ፊትም ፡ መልኩ ፡ እንደ ፡ ሌላው ፡ መልክ ፡ ነበረ ። ፳፪ መሠዊያውም ፡ ቁመቱ ፡ ሦስት ፡ ክንድ ፡ ርዝመቱ ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፡ ሆኖ ፡ ከእንጨት ፡ ተሠርቶ ፡ ነበር ፤ ማዕዘኖቹም ፡ እግሩም ፡ አገዳዎቹም ፡ ከእንጨት ፡ ተሠርተው ፡ ነበር ፤ እርሱም ፡— በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያለችው ፡ ገበታ ፡ ይህች ፡ ናት ፡ አለኝ ። ፳፫ ለመቅደሱና ፡ ለተቀደሰው ፡ ስፍራ ፡ ሁለት ፡ መዝጊያዎች ፡ ነበሩአቸው ። ፳፬ ለእያንዳንዱ ፡ መዝጊያም ፡ ሁለት ፡ ተዘዋዋሪ ፡ ሳንቃዎች ፡ ነበሩት ፤ ለአንዱ ፡ መዝጊያ ፡ ሁለት ፡ ለሌላውም ፡ መዝጊያ ፡ ሁለት ፡

፳፭ ሳንቃዎች ፡ ነበሩት ። በግንቡም ፡ ላይ ፡ በተቀረጹት ፡ ዓይነት ፡ በእነዚህ ፡ በመቅደሱ ፡ መዝጊያዎች ፡ ላይ ፡ ኪሩቤልና ፡ የዘንባባ ፡ ዛፎች ፡ ተቀርጸው ፡ ነበር ፤ በስተ ፡ ውጭም ፡ ባለው ፡ በደጀ ፡ ሰላሙ ፡ ፊት ፡ የእንጨት ፡ መድረክ ፡ ፳፮ ነበረ ። በደጀ ፡ ሰላሙም ፡ በሁለቱ ፡ ወገን ፡ በዚህና ፡ በዚያ ፡ የዓይነ ፡ ርግብ ፡ መስኮቶችና ፡ የተቀረጹ ፡ የዘንባባ ፡ ዛፎች ፡ ነበሩበት ፤ የመቅደሱም ፡ ጓዳዎችና ፡ የእንጨቱ ፡ መድረክ ፡ እንዲሁ ፡ ነበሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፪ ።

፩ በውጭም ፡ አደባባይ ፡ በሰሜኑ ፡ መንገድ ፡ አወጣኝ ፥ በልዩውም ፡ ስፍራ ፡ አንጻርና ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ባለው ፡ ግቢ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ወዳ ፪ ለው ፡ ዕቃ ፡ ቤት ፡ አገባኝ ። መቶ ፡ ክንድ ፡ በሆነው ፡ ርዝመት ፡ ፊት ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ መዝጊያ ፡ ነበረ ፡ ወርዱም ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። ፫ በውስጠኛውም ፡ አደባባይ ፡ በሀያው ፡ ክንድ ፡ አንጻር ፡ በውጭውም ፡ አደባባይ ፡ በወለሉ ፡ አንጻር ፡ በሦስት ፡ ደርብ ፡ በትይዩ ፡ የተሠራ ፡ ፬ መተላለፊያ ፡ ነበረ ። በዕቃ ፡ ቤቶቹም ፡ ፊት ፡ በስተ ፡ ውስጥ ፡ ወርዱ ፡ አሥር ፡ ክንድ ፡ ርዝመቱ ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፡ መንገድ ፡ ነበረ ፤ መዝጊያዎቻቸውም ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ይመለ ፭ ከቱ ፡ ነበር ። መተላለፊያውም ፡ አሳጥሮአቸዋልና ፡ ላይኞቹ ፡ ዕቃ ፡ ቤቶች ፡ ከመካከለኞቹና ፡ ፮ ከታችኞቹ ፡ ይልቅ ፡ አጫጭር ፡ ነበሩ ። በሦስትም ፡ ደርብ ፡ ተሠርተው ፡ ነበርና ፥ በአደባባዩም ፡ እንዳሉት ፡ አዕማድ ፥ አዕማድ ፡ አልነበሩላቸውምና ፡ ስለዚህ ፡ ላይኞቹ ፡ ከመካከለኞቹና ፡ ከታችኞቹ ፡ ይልቅ ፡ ጠባብ ፡ ነበሩ ። ፯ በውጭ ፡ በዕቃ ፡ ቤቶቹ ፡ አጠገብ ፡ ያለው ፥ ወደ ፡ ውጭው ፡ አደባባይ ፡ የሚመለከተው ፡ ቅጥር ፥ በዕቃ ፡ ቤቶች ፡ ትይዩ ፡ የሆነ ፥ ርዝ ፰ መቱ ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ነበረ ። በመቅደሱ ፡ ፊት ፡ የነበሩት ፡ ዕቃ ፡ ቤቶች ፡ ርዝመታቸው ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ ሲሆን ፡ በውጭው ፡ አደባባይ ፡ በኩል ፡ የነበሩት ፡ ዕቃ ፡ ቤቶች ፡ ርዝመታቸው ፡ ፱ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ነበረና ። ከእነዚህም ፡ ዕቃ ፡ ቤቶች ፡ በታች ፡ በስተ ፡ ምሥራቅ ፡ በኩል ፥ ሰው ፡ ከውጭው ፡ አደባባይ ፡ የሚገባበት ፡ መግቢያ ፡ ነበረ ። ይህም ፡ በቅጥሩ ፡ ራስ ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ።

፲ በደቡብም ፡ በኩል ፡ በልዩው ፡ ስፍራና ፡ በግ ፲፩ ቢው ፡ አንጻር ፡ ዕቃ ፡ ቤቶች ፡ ነበሩ ። በስተ ፡ ፊታቸውም ፡ የነበረ ፡ መንገድ ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡ እንደ ፡ ዕቃ ፡ ቤቶቹ ፡ መንገድ ፡ ምስያ ፡ ነበረ ። ርዝመታቸውም ፡ ወርዳቸውም ፡ መውጫቸውም ፡ ሥርዓታቸውም ፡ መዝጊያዎ ፲፪ ቻቸውም ፡ በዚያው ፡ ልክ ፡ ነበረ ። በደቡብም ፡ በኩል ፡ ካሉት ፡ ዕቃ ፡ ቤቶች ፡ በታች ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ በቅጥሩ ፡ ራስ ፡ አጠገብ ፡ መግቢያ ፡ ነበረ ።

፲፫ እንዲህም ፡ አለኝ ፦ በልዩ ፡ ስፍራ ፡ አንጻር ፡ በሰሜንና ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ያሉ ፡ ዕቃ ፡ ቤቶች ፥ እነርሱ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚቀርቡ ፡ ካህናት ፡ ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ የተቀደሰውን ፡ ምግብ ፡ የሚበሉባቸው ፡ ቤቶች ፡ ናቸው ። ስፍራው ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ፡ በዚያ ፡ የተቀደሰውን ፡ ነገር ፡ የእህሉን ፡ ቍርባን ፡ የኃጢአቱንና ፡ የበደሉን ፡ ፲፬ መሥዋዕት ፡ ያኖራሉ ። ካህናቱም ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ ከመቅደሱ ፡ በውጭው ፡ አደባባይ ፡ አይወጡም ፤ የሚያገለግሉበትን ፡ ልብሳቸውን ፡ ግን ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ፡ በዚያ ፡ ያኖሩታል ፥ ሌላም ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡ ወደ ፡ ሕዝብ ፡ ይወጣሉ ።

፲፭ ውስጠኛውንም ፡ ቤት ፡ ለክቶ ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ በሚመለከት ፡ በር ፡ መንገድ ፡ አወጣኝ ፡ እርሱንም ፡ በዙሪያው ፡ ለካው ። ፲፮ የምሥራቁን ፡ ወገን ፡ በመለኪያ ፡ ዘንግ ፡ አም ፲፯ ስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ። ዞረም ፥ የሰሜኑንም ፡ ወገን ፡ በመለኪያ ፡ ዘንግ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ። ዞረም ፥ ፲፰ የደቡቡንም ፡ ወገን ፡ በመለኪያ ፡ ዘንግ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ። ዞረም ፥ ፲፱ የምዕራቡንም ፡ ወገን ፡ በመለኪያ ፡ ዘንግ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ለካ ። በአራቱ ፡ ፳ ወገን ፡ ለካው ። የተቀደሰውንና ፡ ያልተቀደሰውን ፡ ይለይ ፡ ዘንድ ፡ ርዝመቱ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፡ ቅጥር ፡ በዙሪያው ፡ ነበረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፫ ።

፩ ወደ ፡ ምሥራቅም ፡ ወደሚመለከተው ፡ ፪ በር ፡ አመጣኝ ። እነሆም ፥ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ክብር ፡ ከምሥራቅ ፡ መንገድ ፡ መጣ ፤ ድምፁም ፡ እንደ ፡ ብዙ ፡ ውኆች ፡ ይተምም ፡ ነበር ፥ ከክብሩም ፡ የተነሣ ፡ ምድር ፡ ታበራ ፡ ፫ ነበር ። ያየሁትም ፡ ራእይ ፡ ከተማይቱን ፡ ለማጥፋት ፡ በመጣሁ ፡ ጊዜ ፡ እንዳየሁት ፡ ራእይ ፡ ነበረ ፤ ራእዩም ፡ በኮቦር ፡ ወንዝ ፡ እንዳየሁት ፡ ራእይ ፡ ነበረ ፤ እኔም ፡ በግምባሬ ፡ ተደፋሁ ። ፬ የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ በሚመለከት ፡ በር ፡ ወደ ፡ መቅደሱ ፡ ገባ ። ፭ መንፈሱም ፡ አነሣኝ ፡ ወደ ፡ ውስጠኛውም ፡ አደባባይ ፡ አገባኝ ፤ እነሆም ፥ የእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ መቅደሱን ፡ መልቶት ፡ ነበር ።

፮ በመቅደሱም ፡ ሆኖ ፡ የሚናገረኝን ፡ ሰማሁ ፥ ፯ በአጠገቤም ፡ ሰው ፡ ቆሞ ፡ ነበር ። እንዲህም ፡ አለኝ ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ለዘላለም ፡ የምቀመጥበት ፡ የዙፋኔ ፡ ስፍራና ፡ የእግሬ ፡ ጫማ ፡ መረገጫ ፡ ይህ ፡ ነው ። ዳግመኛም ፡ የእስራኤል ፡ ቤትና ፡ ነገሥታቶቻቸው ፡ በግልሙትናቸውና ፡ በከፍታዎቻቸው ፡ ባለው ፡ በነገሥታቶቻቸው ፡ ሬሳ ፡ ቅዱስ ፡ ስሜን ፡ አያረክሱም ፤ መድረካቸውን ፡ ፰ በመድረኬ ፡ አጠገብ ፥ መቃናቸውንም ፡ በመቃኔ ፡ አጠገብ ፡ አድርገዋልና ። በእኔና ፡ በእነር

ሱም ፡ መካከል ፡ ግንብ ፡ ብቻ ፡ ነበረ ፤ በሠሩ
ትም ፡ ርኵሰት ፡ ቅዱስ ፡ ስሜን ፡ አረከሱ ፤ ስለ
፱ ዚህ ፡ በቍጣዬ ፡ አጠፋኋቸው ። አሁንም ፡ ግል
ሙትናቸውንና ፡ የነገሥታቶቻቸውን ፡ ሬሳ ፡
ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ያርቁ ÷ እኔም ፡ ለዘላለም ፡ በመ
ካከላቸው ፡ አድራለሁ ።

፲ አንተም ፡ የሰው ፡ ልጅ ÷ ከኃጢአታቸው ፡
የተነሣ ፡ ያፍሩ ፡ ዘንድ ፡ ለእስራኤል ፡ ወገን ፡
ይህን ፡ ቤት ፡ አሳያቸው ፡ አምሳያውንም ፡
፲፩ ይለኩ ። ከሠሩትም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ የተነሣ ፡
ቢያፍሩ ÷ የቤቱን ፡ መልክና ፡ ምሳሌውን ፡ መው
ጫውንም ፡ መግቢያውንም ፡ ሥርዓቱንም ፡
ሕጉንም ፡ ሁሉ ፡ አስታውቃቸው ፤ ሥርዓቱንና ፡
ሕጉን ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ያደርጉትም ፡
፲፪ ዘንድ ፡ በፊታቸው ፡ ጻፈው ። የቤቱ ፡ ሕግ ፡
ይህ ፡ ነው ፤ በተራራው ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ዳርቻው ፡
ሁሉ ፡ በዙሪያው ፡ ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ የተቀደሰ ፡
ይሆናል ። እነሆ ÷ የቤቱ ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ።

፲፫ የመሠዊያውም ፡ ልክ ፡ በክንድ ፡ ይህ ፡ ነው ÷
ክንዱም ፡ ክንድ ፡ ተጋት ፡ ነው ። የመሠረቱም ፡
ቁመቱ ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡
ነው ÷ አንድ ፡ ስንዝርም ፡ ከፈፍ ፡ ዳር ፡ ዳሩን ፡
በዙሪያው ፡ አለ ፤ የመሠዊያው ፡ መሠረት ፡ እን
፲፬ ዲሁ ፡ ነው ። በመሬቱም ፡ ላይ ፡ ካለው ፡ መሠ
ረት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታችኛው ፡ እርከን ፡ ድረስ ፡
ሁለት ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ነው ፤
ከትንሹም ፡ እርከን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ትልቁ ፡
እርከን ፡ ድረስ ፡ አራት ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ አንድ ፡
፲፭ ክንድ ፡ ነው ። ምድጃውም ፡ አራት ፡ ክንድ ፡
ነው ፤ በምድጃውም ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ወደ ፡
ላይ ፡ ከፍ ፡ የሚሉ ፡ አራት ፡ ቀንዶች ፡ አሉበት ።
፲፮ የምድጃውም ፡ ርዝመት ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡
ክንድ ፡ ወርዱም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ክንድ ፡
ነው ÷ አራቱም ፡ ማዕዘን ፡ ትክክል ፡ ነው ።
፲፯ የእርከኑም ፡ ርዝመት ፡ አሥራ ፡ አራት ፡ ክንድ ፡
ወርዱም ፡ አሥራ ፡ አራት ፡ ክንድ ፡ ነው ÷ አራ
ቱም ፡ ማዕዘን ፡ ትክክል ፡ ነው ፤ በዙሪያውም ፡
ያለው ፡ ከፈፍ ፡ እኩል ፡ ክንድ ፡ ነው ÷ መሠረ
ቱም ፡ በዙሪያው ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ ነው ፤ ደረጃ
ዎቹም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይመለከታሉ ።

፲፰ እንዲህም ፡ አለኝ ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ የሚ
ቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርቡበት ፡ ዘንድ ፡
ደሙንም ፡ ይረጩበት ፡ ዘንድ ፡ በሚሠሩበት ፡
፲፱ ቀን ፡ የመሠዊያው ፡ ሕግ ፡ ይህ ፡ ነው ። ያገለግ
ሉኝ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ለሚቀርቡ ፡ ከሳዶቅ ፡
ዘር ፡ ለሚሆኑ ፡ ለሌዋውያኑ ፡ ካህናት ፡ ለኃጢ
አት ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆነውን ፡ ወይፈን ፡ ትሰ
ጣቸዋለህ ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።
፳ ከደሙም ፡ ትወስዳለህ ÷ በአራቱ ፡ ቀንዶቹም ፡
በእርከኑም ፡ በአራቱ ፡ ማዕዘን ፡ ላይ ፡ በዙሪያ
ውም ፡ ባለው ፡ ከፈፍ ፡ ላይ ፡ ትረጨዋለህ ፤
እንዲሁ ፡ ታነጻዋለህ ፡ ታስተሰርይለትማለህ ።
፳፩ ለኃጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆነውን ፡ ወይ
ፈን ፡ ትወስዳለህ ÷ በመቅደሱም ፡ ውጭ ፡
፳፪ በቤቱ ፡ በታዘዘው ፡ ስፍራ ፡ ይቃጠላል ። በሁ
ለተኛውም ፡ ቀን ፡ ለኃጢአት ፡ መሥዋዕት ፡
የሚሆነውን ፡ ነውር ፡ የሌለበትን ፡ አውራ ፡
ፍየል ፡ ታቀርባለህ ፤ በወይፈኑም ፡ እንዳነጹት ፡
፳፫ እንዲሁ ፡ መሠዊያውን ፡ ያነጹበታል ። ማንጻ
ቱንም ፡ ከፈጸምህ ፡ በኋላ ፡ ነውር ፡ የሌለበትን ፡
ወይፈን ፡ ከመንጋውም ፡ የወጣውን ፡ ነውር ፡
፳፬ የሌለበትን ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ታቀርባለህ ። በእግዚ
አብሔርም ፡ ፊት ፡ ታቀርባቸዋለህ ÷ ካህናቱም ፡
ጨው ፡ ይጨምሩባቸዋል ÷ የሚቃጠለውንም ፡
መሥዋዕት ፡ አድርገው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያቀ
፳፭ ርቡአቸዋል ። ሰባት ፡ ቀንም ፡ በየዕለቱ ፡ ለኃ
ጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆነውን ፡ አውራ ፡
ፍየልን ፡ ታቀርባለህ ÷ ነውርም ፡ የሌለባቸውን ፡
አንድ ፡ ወይፈን ፡ ከመንጋውም ፡ የወጣውን ፡
፳፮ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ያቀርባሉ ። ሰባት ፡ ቀን ፡
ለመሠዊያው ፡ ያስተሰርያሉ ፡ ያነጹትማል ÷
፳፯ እንዲሁም ፡ ይቀድሱታል ። ቀኖቹንም ፡ በፈ
ጸሙ ፡ ጊዜ ፡ በስምንተኛው ፡ ቀን ፡ ከዚያም ፡
በኋላ ፡ ካህናቱ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕታ
ችሁን ፡ የደኅንነትንም ፡ መሥዋዕታችሁን ፡
በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ያደርጋሉ ፤ እኔም ፡ እቀበ
ላችኋለሁ ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፬ ።

፩ ወደ ፡ ምሥራቅም ፡ ወደሚመለከተው ፡ በስተ ፡
ውጭ ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ መቅደሱ ፡ በር ፡ አመ
፪ ጣኝ ፤ ተዘግቶም ፡ ነበር ። እግዚአብሔርም ፦
ይህ ፡ በር ፡ ተዘግቶ ፡ ይኖራል ፡ እንጂ ፡ አይከፈ
ትም ÷ ሰውም ፡ አይገባበትም ፤ የእስራኤል ፡
አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ገብቶበታልና ፡ ተዘ
፫ ግቶ ፡ ይኖራል ። አለቃው ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንጀራ ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡
ይቀመጥበታል ፤ በበሩ ፡ ደጅ ፡ ሰላም ፡ መንገድ ፡
ይገባል ፡ በዚያም ፡ መንገድ ፡ ይወጣል ።

፬ በሰሜኑም ፡ በር ፡ መንገድ ፡ በቤቱ ፡ ፊት ፡
አመጣኝ ፤ እኔም ፡ አየሁ ÷ እነሆም ÷ የእግዚአ
ብሔር ፡ ክብር ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ሞል
ቶት ፡ ነበር ፤ እኔም ፡ በግምባሬ ፡ ተደፋሁ ።
፭ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፦ የሰው ፡
ልጅ ፡ ሆይ ÷ ልብ ፡ አድርግ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔ
ርም ፡ ቤት ፡ ሥርዓትና ፡ ሕግ ፡ ሁሉ ፡ የምናገር
ህን ፡ ሁሉ ፡ በዓይንህ ፡ ተመልከት ፡ በጆሮህም ፡
ስማ ፤ የቤቱንም ፡ መግቢያ ፡ የመቅደሱንም ፡
፮ መውጫ ፡ ሁሉ ፡ ልብ ፡ አድርግ ። ለዓመፀኛው ፡
ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ እንዲህ ፡ በል ፦ ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እናንተ ፡ የእስ
፯ ራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ እንጀራዬን ÷ ስብንና ፡
ደምን ÷ በምታቀርቡበት ፡ ጊዜ ፡ በመቅደሴ ፡
ውስጥ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ቤቴንም ፡ ያረክሱ ፡
ዘንድ ፡ በልባቸውና ፡ በሥጋቸው ፡ ያልተገረዙ
ትን ፡ እንግዶችን ፡ ሰዎች ፡ አግብታችኋልና ÷
እነርሱም ፡ በርኵሰታቸው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ይጨ

መሩ ፡ ዘንድ ፡ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ አፍርሰዋልና ፡
፰ ርኵሰታችሁ ፡ ሁሉ ፡ ይብቃችሁ ። በመቅደሴ ፡
ውስጥ ፡ ለራሳችሁ ፡ ሥርዓቴን ፡ ጠባቂዎች ፡
አደረጋችሁ ፡ እንጂ ፡ የተቀደሰውን ፡ ነገሬን ፡
ሥርዓት ፡ አልጠበቃችሁም ።
፱ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ ካሉት ፡ ሁሉ ፡
በልቡና ፡ በሥጋው ፡ ያልተገረዘ ፡ እንግዳ ፡
፲ ሁሉ ፡ ወደ ፡ መቅደሴ ፡ አይግባ ። ከእኔ ፡ ዘንድ ፡
የራቁ ፥ እስራኤልም ፡ በሳቱ ፡ ጊዜ ፡ ጣዖታቸ
ውን ፡ ተከትለው ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ የሳቱ ፡ ሌዋው
፲፩ ያን ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ይሸከማሉ ። ነገር ፡ ግን ፡
በመቅደሴ ፡ ውስጥ ፡ አገልጋዮች ፡ ይሆናሉ ፥
በቤቱም ፡ በሮች ፡ በረኞች ፡ ይሆናሉ ፡ በቤቱም ፡
ውስጥ ፡ ያገለግላሉ ፤ ለሕዝቡም ፡ የሚቃጠለ
ውን ፡ መሥዋዕትና ፡ ሌላ ፡ መሥዋዕቱን ፡ ያር
ዳሉ ፥ ያገለግሉአቸውም ፡ ዘንድ ፡ በፊታቸው ፡
፲፪ ይቆማሉ ። በጣዖቶቻቸውም ፡ ፊት ፡ አገልግለ
ዋቸው ፡ ነበሩና ፥ ለእስራኤልም ፡ ቤት ፡ የኃጢ
አት ፡ ዕንቅፋት ፡ ሆነዋልና ፡ ስለዚህ ፡ እጄን ፡
በላያቸው ፡ አንሥቻለሁ ፥ ኃጢአታቸውንም ፡
ይሸከማሉ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።
፲፫ ካህናትም ፡ ይሆኑኝ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አይቀር
ቡም ፥ ወደ ፡ ተቀደሰውም ፡ ነገሬና ፡ ወደ ፡
ቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፡ ነገር ፡ አይቀርቡም ፤ እፍረ
ታቸውንና ፡ የሠሩትንም ፡ ርኵሰታቸውን ፡ ይሸ
፲፬ ከማሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ ለአገልግሎቱ ፡ ሁሉና ፡
በእርሱ ፡ ውስጥ ፡ ለሚደረገው ፡ ሁሉ ፡ የቤቱን ፡
ሥርዓት ፡ ጠባቂዎች ፡ አደርጋቸዋለሁ ።
፲፭ ነገር ፡ ግን ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከእኔ ፡
ዘንድ ፡ በሳቱ ፡ ጊዜ ፡ የመቅደሴን ፡ ሥርዓት ፡
የጠበቁ ፡ የሳዶቅ ፡ ልጆች ፡ ሌዋውያን ፡ ካህናት ፡
ያገለግሉኝ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይቀርባሉ ፤
ስቡንና ፡ ደሙንም ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡
በፊቴ ፡ ይቆማሉ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።
፲፮ ወደ ፡ መቅደሴም ፡ ይገባሉ ፡ ያገለግሉኝም ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ ገበታዬ ፡ ይቀርባሉ ፡ ሥርዓቴ
፲፯ ንም ፡ ይጠብቃሉ ። ወደ ፡ ውስጠኛውም ፡ አደ
ባባይ ፡ በር ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ የተልባ ፡ እግር ፡ ልብስ ፡
ይልበሱ ፤ በውስጠኛውም ፡ አደባባይ ፡ በርና ፡
በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ባገለገሉ ፡ ጊዜ ፡ ከበግ ፡ ጠጕር ፡
፲፰ አንዳች ፡ ነገር ፡ በላያቸው ፡ አይሁን ። በራሳ
ቸው ፡ ላይ ፡ የተልባ ፡ እግር ፡ መጠምጠሚያ ፡
ይሁን ፥ በወገባቸውም ፡ ላይ ፡ የተልባ ፡ እግር ፡
ሱሪ ፡ ይሁን ፤ የሚያወዛም ፡ ነገር ፡ አይታጠቁ ።
፲፱ ወደ ፡ ውጭውም ፡ አደባባይ ፡ ወደ ፡ ሕዝብ ፡
በወጡ ፡ ጊዜ ፡ ያገለገሉበትን ፡ ልብሳቸውን ፡
ያውልቁ ፡ በተቀደሰውም ፡ ዕቃ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡
ያኑሩት ፥ ሕዝቡንም ፡ በልብሳቸው ፡ እንዳይቀ
፳ ድሱ ፡ ሌላውን ፡ ልብስ ፡ ይልበሱ ። ራሳቸው
ንም ፡ አይላጩ ፡ የራሳቸውንም ፡ ጠጕር ፡ ይከር
፳፩ ክሙ ፡ እንጂ ፡ ጠጕራቸውን ፡ አያሳድጉ ። ካህና
ቱም ፡ ሁሉ ፡ በውስጠኛው ፡ አደባባይ ፡ ሲገቡ ፡
፳፪ የወይን ፡ ጠጅ ፡ አይጠጡ ። መበለቲቱንና ፡ የተ
ፈታችይቱን ፡ አያግቡ ፤ ከእስራኤል ፡ ቤት ፡ ዘር ፡
ግን ፡ ድንግሊቱን ፡ ወይም ፡ የካህን ፡ ሚስት ፡
፳፫ የነበረችይቱን ፡ መበለት ፡ ያግቡ ። በተቀደሰ
ውና ፡ ባልተቀደሰው ፡ መካከል ፡ ይለዩ ፡ ዘንድ ፡
ሕዝቤን ፡ ያስተምሩ ፥ ንጹሕና ፡ ንጹሕ ፡ ባልሆ
ነው ፡ መካከል ፡ ይለዩ ፡ ዘንድ ፡ ያሳዩአቸው ።
፳፬ ክርክርም ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ለመፍረድ ፡ ይቁሙ ፤
እንደ ፡ ፍርዴ ፡ ይፍረዱ ፤ በበዓላቴ ፡ ሁሉ ፡
ሕጌንና ፡ ሥርዓቴን ፡ ይጠብቁ ፥ ሰንበታቴንም ፡
፳፭ ይቀድሱ ። እንዳይረክሱም ፡ ወደ ፡ ሞተ ፡ ሰው ፡
አይግቡ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለአባት ፡ ወይም ፡ ለእናት ፡
ወይም ፡ ለወንድ ፡ ልጅ ፡ ወይም ፡ ለሴት ፡ ልጅ ፡
ወይም ፡ ለወንድም ፡ ወይም ፡ ላልተዳረች ፡
፳፮ እኅት ፡ ይርከሱ ። ከነጻም ፡ በኋላ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡
፳፯ ይቈጠርለት ። በመቅደስም ፡ ውስጥ ፡ ያገለግል ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ ውስጠኛው ፡ አደባባይ ፡ ወደ ፡
መቅደሱ ፡ በሚገባበት ፡ ቀን ፥ የኃጢአትን ፡
መሥዋዕት ፡ ያቅርብ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔር ።
፳፰ ርስት ፡ ይሆንላቸዋል ፤ እኔ ፡ ርስታቸው ፡ ነኝ ፤
በእስራኤልም ፡ ዘንድ ፡ ግዛት ፡ አትስጡአቸው ፤
፳፱ እኔ ፡ ግዛታቸው ፡ ነኝ ። የእህሉን ፡ ቍርባንና ፡
የኃጢአትን ፡ መሥዋዕት ፡ የበደልንም ፡ መሥ
ዋዕት ፡ ይበላሉ ፤ በእስራኤልም ፡ ዘንድ ፡
እርም ፡ የሆነው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ለእነርሱ ፡
፴ ይሆናል ። የበኵራቱ ፡ ሁሉ ፡ መጀመሪያ ፡ ከየ
ዓይነቱ ፡ ከቍርባናችሁም ፡ ሁሉ ፡ የማንሣት ፡
ቍርባን ፡ ሁሉ ፡ ለካህናት ፡ ይሆናል ፤ በቤታች
ሁም ፡ ውስጥ ፡ በረከት ፡ ያድር ፡ ዘንድ ፡ የዱቄ
ታችሁን ፡ በኵራት ፡ ለካህናቱ ፡ ትሰጣላችሁ ።
፴፩ የበከተውንና ፡ የተሰበረውን ፥ ወፍ ፡ ወይም ፡
እንስሳ ፡ ቢሆን ፥ ካህናት ፡ አይብሉት ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፭ ።

፩ ርስትም ፡ አድርጋችሁ ፡ ምድርን ፡ በዕጣ ፡
በምታካፍሉበት ፡ ጊዜ ፡ ከምድር ፡ የተቀደሰ
ውን ፡ የዕጣ ፡ ክፍል ፡ መባ ፡ አድርጋችሁ ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ታቀርባላችሁ ። ርዝመቱ ፡ ሀያ ፡
አምስት ፡ ሺህ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ ሀያ ፡ ሺህ ፡
ክንድ ፡ ይሆናል ፤ በዳርቻው ፡ ሁሉ ፡ ዙሪያውን ፡
፪ የተቀደሰ ፡ ይሆናል ። ከእርሱም ፡ ርዝመቱ ፡ አም
ስት ፡ መቶ ፡ ወርዱም ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡
አራት ፡ ማዕዘን ፡ የሆነ ፡ ቦታ ፡ ለመቅደሱ ፡ ይሆ
ናል ፤ በዙሪያውም ፡ ባዶ ፡ ስፍራ ፡ የሚሆን ፡
፫ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ይሆናል ። ከዚያው ፡ ልክ ፡
ደግሞ ፡ ርዝመቱ ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ክንድ ፡
ወርዱም ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፡ ስፍራ ፡
ትለካለህ ፤ በእርሱም ፡ ውስጥ ፡ ቅድስተ ፡ ቅዱ
፬ ሳን ፡ የሆነ ፡ መቅደስ ፡ ይሆናል ። ከምድርም ፡
የተቀደሰ ፡ የዕጣ ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ፤ እግዚአብ
ሔርን ፡ ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡ ለሚቀርቡ ፡ ለመቅ
ደሱ ፡ አገልጋዮች ፡ ለካህናቱ ፡ ይሆናል ፥ ለቤ
ቶቻቸውም ፡ የሚሆን ፡ ስፍራ ፡ ለመቅደስም ፡
፭ የሚሆን ፡ የተቀደሰ ፡ ስፍራ ፡ ይሆናል ። ርዝመ

ቱም፡ሀያ፡አምስት፡ሺህ፡ወርዱም፡አሥር፡ሺህ፡የሆነ፡ዕፍራ፡ለቤቱ፡አገልጋዮች፡ለሌዋውያን፡ይሆናል፥ለሚቀመጡባቸውም፡ከተሞች፡ለራሳቸውም፡የርስት፡ይዞታ፡ይሆ ፮፡ ናል። ለከተማይቱም፡ይዞታ፡በተቀደሰው፡የዕጣ፡ክፍል፡መባ፡አጠገብ፡ወርዱ፡አምስት፡ሺህ፡ርዝመቱም፡ሀያ፡አምስት፡ሺህ፡የሆነውን፡ስፍራ፡ታደርጋላችሁ። እርሱም፡ ፯፡ ለእስራኤል፡ቤት፡ሁሉ፡ይሆናል። ለአለቃውም፡የሆነ፡የዕጣ፡ክፍል፡በተቀደሰው፡መባና፡በከተማይቱ፡ይዞታ፡አጠገብ፡በዚህና፡በዚያ፡ይሆናል፤በተቀደሰው፡መባና፡በከተማይቱ፡ይዞታ፡ፊት፡በምዕራብ፡በኩል፡ወደ፡ምዕራብ፡በምሥራቅም፡በኩል፡ወደ፡ምሥራቅ፡ይሆናል፤ርዝመቱም፡እንደ፡አንድ፡ነገድ፡ዕጣ፡ክፍል፡ሆኖ፡ከምድሩ፡ከምዕራቡ፡ዳርቻ፡ጀምሮ፡እስከ፡ምሥራቁ፡ዳርቻ፡ ፰፡ ድረስ፡ይሆናል። ይህም፡በእስራኤል፡ዘንድ፡ይዞታ፡ይሆንለታል፥አለቆቼም፡ለእስራኤል፡ቤት፡ምድሪቱን፡እንደ፡ነገዳቸው፡መጠን፡ይሰጡአቸዋል፡እንጂ፡ሕዝቤን፡ከእንግዲህ፡ወዲህ፡አያስጨንቋቸውም።

፱፡ ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡—የእስራኤል፡አለቆች፡ሆይ፥ይብቃችሁ፤ግፍንና፡ብዝበዛን፡አስወግዱ፥ፍርድንና፡ጽድቅንም፡አድርጉ፤ቅሚያችሁን፡ከሕዝቤ፡ላይ፡ ፲፡ አርቁ፥ይላል፡ጌታ፡እግዚአብሔር። እውነተኛ፡ሚዛን፡እውነተኛም፡የኢፍ፡መስፈሪያ፡እውነተኛም፡የባዶስ፡መስፈሪያ፡ይሁንላችሁ። ፲፩፡ የኢፍና፡የባዶስ፡መስፈሪያ፡አንድ፡ይሁን፤የባዶስ፡መስፈሪያ፡የቆሮስ፡መስፈሪያ፡አሥረኛ፡ክፍል፥የኢፍ፡መስፈሪያውም፡የቆሮስ፡መስፈሪያ፡አሥረኛ፡ክፍል፡ይሁን። መስፈሪያው፡እንደ፡ቆሮስ፡መስፈሪያ፡ይሁን። ፲፪፡ ሰቅሉም፡ሀያ፡አቦሊ፡ይሁን፤ሀያ፡ሰቅል፥ሀያ፡አምስት፡ሰቅል፥አሥራ፡አምስት፡ሰቅል፥ምናን፡ይሁንላችሁ።

፲፫፡ የምታቀርቡት፡መባ፡ይህ፡ነው፤ከአንድ፡ቆሮስ፡መስፈሪያ፡ስንዴ፡የኢፍ፡መስፈሪያ፡ስድስተኛ፡ክፍል፥ከአንድም፡ቆሮስ፡መስፈሪያ፡ገብስ፡የኢፍ፡መስፈሪያ፡ስድስተኛ፡ ፲፬፡ ክፍል፡ትሰጣላችሁ። የዘይቱም፡ደንብ፥ከእያንዳንዱ፡የቆሮስ፡መስፈሪያ፡የባዶስን፡አሥረኛ፡ክፍል፡ትሰጣላችሁ፤አሥር፡የባዶስ፡መስፈሪያ፡አንድ፡የቆሮስ፡መስፈሪያ፡ነውና። ፲፭፡ ውኃም፡ካለበት፡ከእስራኤል፡ማሰማርያ፡ከመንጋው፡ከሁለቱ፡መቶ፡አንዱን፡የበግ፡ጠቦት፡ትሰጣላችሁ፤ይህ፡ያስተሰርይላችሁ፡ዘንድ፡ለእህል፡ቍርባንና፡ለሚቃጠል፡መሥዋዕት፡ለደኅንነትም፡መሥዋዕት፡ይሆናል፥ ፲፮፡ ይላል፡ጌታ፡እግዚአብሔር። የአገሩም፡ሕዝብ፡ሁሉ፡ይህን፡መባ፡ለእስራኤል፡አለቃ፡ይሰ ፲፯፡ ጣሉ። በየበዓላቱም፡በየመባቻውም፡በየሰንበታቱም፡በእስራኤልም፡ቤት፡ዓመት፡በዓል፡ሁሉ፡የሚቃጠለውን፡መሥዋዕትና፡የእህሉን፡ቍርባን፡የመጠጡንም፡ቍርባን፡መስጠት፡በአለቃው፡ላይ፡ይሆናል፤እርሱ፡ለእስራኤል፡ቤት፡ያስተሰርይ፡ዘንድ፡የኃጢአቱን፡መሥዋዕትና፡የእህሉን፡ቍርባን፡የሚቃጠለውን፡መሥዋዕትና፡የደኅንነቱን፡መሥዋዕት፡ያቀርባል።

፲፰፡ ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡—በመጀመሪያው፡ወር፡ከወሩም፡በመጀመሪያው፡ቀን፡ነውር፡የሌለበትን፡ወይፈን፡ውሰድ፡መቅደሱንም፡አንጻ። ፲፱፡ ካህኑም፡ከኃጢአቱ፡መሥዋዕት፡ደም፡ወስዶ፡በመቅደሱ፡መቃኖችና፡በመሠዊያው፡እርከን፡በአራቱ፡ማዕዘን፡በውስጠኛውም፡አደባባይ፡በበሩ፡መቃኖች፡ላይ፡ይርጨው። ፳፡ ከወሩም፡በሰባተኛው፡ቀን፡እንዲሁ፡አድርግ፥ይኸውም፡ስለ፡ሳተውና፡ስላላወቀው፡ሁሉ፡ነው። እንዲሁም፡ስለ፡ቤቱ፡አስተስርዩ።

፳፩፡ በመጀመሪያ፡ወር፡ከወሩም፡በአሥራ፡አራተኛው፡ቀን፡የፋሲካን፡በዓል፡ታደርጋላችሁ። እስከ፡ሰባት፡ቀንም፡ድረስ፡ቂጣ፡እንጀራ፡ትበላላችሁ። ፳፪፡ በዚያም፡ቀን፡አለቃው፡ለራሱና፡ለአገሩ፡ሕዝብ፡ሁሉ፡የኃጢአት፡መሥዋዕት፡የሚሆነውን፡ወይፈን፡ያቅርብ። ፳፫፡ በበዓሉም፡በሰባቱ፡ቀኖች፡የሚቃጠለውን፡መሥዋዕት፡ለእግዚአብሔር፡ያቅርብ፤ሰባቱን፡ቀኖች፡በየዕለቱ፡ነውር፡የሌለባቸውን፡ሰባት፡ወይፈንና፡ሰባት፡አውራ፡በጎች፡ያቅርብ፤ለኃጢአትም፡መሥዋዕት፡በየዕለቱ፡አንድ፡አውራ፡ፍየል፡ያቅርብ። ፳፬፡ ለአንድም፡ወይፈን፡አንድ፡የኢፍ፡መስፈሪያ፡ለአንድም፡አውራ፡በግ፡አንድ፡የኢፍ፡መስፈሪያ፡ለአንድም፡የኢፍ፡መስፈሪያ፡አንድ፡የኢን፡መስፈሪያ፡ዘይት፡ለእህል፡ቍርባን፡ያቅርብ። ፳፭፡ በሰባተኛውም፡ወር፡ከወሩም፡በአሥራ፡አምስተኛው፡ቀን፡በበዓሉ፡ሰባት፡ቀኖች፥የኃጢአቱን፡መሥዋዕት፡የሚቃጠለውንም፡መሥዋዕት፡የእህሉንም፡ቍርባን፡ከዘይቱ፡ጋር፡እንዲሁ፡ያቅርብ።

## ምዕራፍ፡፵፮።

፩፡ ጌታ፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡—በውስጠኛው፡አደባባይ፡ወደ፡ምሥራቅ፡የሚመለከተው፡በር፡ሥራ፡በሚሠራበት፡በስድስቱ፡ቀን፡ተዘግቶ፡ይቈይ፤ነገር፡ግን፡በሰንበት፡ቀንና፡በመባቻ፡ቀን፡ይከፈት። ፪፡ አለቃውም፡በስተ፡ውጭ፡ባለው፡በር፡በደጀ፡ሰላሙ፡መንገድ፡ገብቶ፡በበሩ፡መቃን፡አጠገብ፡ይቁም፥ካህናቱም፡የእርሱን፡የሚቃጠለውን፡መሥዋዕትና፡የደኅንነቱን፡መሥዋዕት፡ያቅርቡ፥እርሱም፡በበሩ፡መድረክ፡ላይ፡ይስገድ፤ከዚያም፡በኋላ፡ይውጣ፥በሩ፡ግን፡እስከ፡ማታ፡ድረስ፡አይዘጋ። ፫፡ የአገሩም፡ሕዝብ፡በዚያ፡በር፡መግቢያ፡በእግዚአብሔር፡

ፊት ፡ በሰንበታትና ፡ በመባቻ ፡ ይስገዱ ። አለቃውም ፡ በሰንበት ፡ ቀን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚያቀርበው ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ነውር ፡ የሌለባቸው ፡ ስድስት ፡ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ ነውርም ፡ የሌለበት ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ይሁን ፤ የእህሉም ፡ ቍርባን ፡ ለአውራ ፡ በጉ ፡ አንድ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ ይሁን ፥ ለጠቦቶቹም ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ እንደሚቻል ፡ ያህል ፡ ይሁን ፥ ለአንዱም ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ አንድ ፡ የኢን ፡ መስፈሪያ ፡ ዘይት ፡ ያቅርብ ። በመባቻም ፡ ቀን ፡ ነውር ፡ የሌለበትን ፡ አንድ ፡ ወይፈን ፥ ነውር ፡ የሌለባቸውንም ፡ ስድስት ፡ ጠቦቶችና ፡ አንድ ፡ አውራ ፡ በግ ፡ ያቅርብ ፤ ለወይፈኑም ፡ አንድ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ ለአውራውም ፡ በግ ፡ አንድ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ ለጠቦቶቹም ፡ እንደ ፡ ተቻለው ፡ ያህል ፥ ለአንዱም ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ አንድ ፡ የኢን ፡ መስፈሪያ ፡ ዘይት ፡ ለእህሉ ፡ ቍርባን ፡ ያቅርብ ። አለቃውም ፡ በሚገባበት ፡ ጊዜ ፡ በበሩ ፡ ደጅ ፡ ሰላም ፡ መንገድ ፡ ይግባ ፡ በዚያውም ፡ ይውጣ ።

የአገሩ ፡ ሕዝብ ፡ ግን ፡ በየክብረ ፡ በዓሉ ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ በሰሜን ፡ በር ፡ በኩል ፡ ሊሰግድ ፡ የሚገባው ፡ በደቡብ ፡ በር ፡ በኩል ፡ ይውጣ ፥ በደቡብም ፡ በር ፡ የሚገባው ፡ በሰሜን ፡ በር ፡ በኩል ፡ ይውጣ ፤ በፊት ፡ ለፊት ፡ ይውጣ ፡ እንጂ ፡ በገባበቱ ፡ በር ፡ አይመለስ ። በሚገቡበት ፡ ጊዜ ፡ አለቃው ፡ በመካከላቸው ፡ ይግባ ፡ በሚወጡበትም ፡ ጊዜ ፡ ይውጣ ። በበዓላትና ፡ በክብረ ፡ በዓል ፡ ቀኖች ፡ የእህሉ ፡ ቍርባን ፡ ለወይፈኑ ፡ አንድ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፥ ለአውራ ፡ በጉ ፡ አንድ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፥ ለጠቦቶቹም ፡ እንደሚቻለው ፡ ያህል ፥ ለኢፍ ፡ መስፈሪያም ፡ አንድ ፡ የኢን ፡ መስፈሪያ ፡ ዘይት ፡ ይሆናል ። አለቃውም ፡ በፈቃዱ ፡ የሚያቀርበውን ፡ መሥዋዕት ፥ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፥ ወይም ፡ በፈቃዱ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚያቀርበውን ፡ የደኅንነቱን ፡ መሥዋዕት ፥ ባቀረበ ፡ ጊዜ ፥ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ የሚመለከተው ፡ በር ፡ ይከፈትለት ፥ በሰንበትም ፡ ቀን ፡ እንደሚያደርግ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የደኅንነቱን ፡ መሥዋዕት ፡ ያቅርብ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ይውጣ ፥ ከወጣም ፡ በኋላ ፡ በሩ ፡ ይዘጋ ።

በየዕለቱም ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ነውር ፡ የሌለበትን ፡ የአንድ ፡ ዓመት ፡ በግ ፡ ጠቦት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያቅርብ ፤ በየማለዳው ፡ ያቅርበው ። ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የእህልን ፡ ቍርባን ፥ በኢን ፡ መስፈሪያ ፡ ሢሶ ፡ ዘይት ፡ የተለወሰ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ ስድስተኛ ፡ እጅ ፡ መልካም ፡ ዱቄትን ፥ በየማለዳው ፡ ያቅርብ ፤ ይህ ፡ በዘላለሙ ፡ ሥርዓት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የዘወትር ፡ የእህል ፡ ቍርባን ፡ ይሁን ። እንዲሁ ፡ ዘወትር ፡ ለሚቃጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ ጠቦቱንና ፡ የእህሉን ፡ ቍርባን ፡ ዘይቱንም ፡ በየማለዳው ፡ ያቅርብ ።

ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— አለቃው ፡ ከልጆቹ ፡ ለአንዱ ፡ ከርስቱ ፡ ስጦታ ፡ ቢሰጥ ፡ ለልጆቹ ፡ ይሁን ፤ የርስት ፡ ይዞታ ፡ ይሆንላቸዋል ። ነገር ፡ ግን ፡ ከባሪያዎቹ ፡ ለአንዱ ፡ ከርስቱ ፡ ስጦታ ፡ ቢሰጥ ፡ እስከ ፡ ነጻነት ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ለእርሱ ፡ ይሁን ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ለአለቃው ፡ ይመለስ ፤ ርስቱ ፡ ግን ፡ ለልጆቹ ፡ ይሁን ። አለቃውም ፡ ሕዝቡን ፡ ከይዞታቸው ፡ ያወጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ከርስታቸው ፡ በግድ ፡ አይውሰድ ፤ ሕዝቤ ፡ ሁሉ ፡ ከይዞታቸው ፡ እንዳይነቀሉ ፡ ከገዛ ፡ ይዞታው ፡ ለልጆች ፡ ርስትን ፡ ይስጥ ።

በበሩም ፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡ መግቢያ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ወደሚመለከተው ፡ ለካህናት ፡ ወደሚሆን ፡ ወደ ፡ ተቀደሰው ፡ ዕቃ ፡ ቤት ፡ አገባኝ ፤ እነሆም ፥ በኋላው ፡ በምዕራብ ፡ በኩል ፡ አንድ ፡ ስፍራ ፡ ነበረ ። እርሱም ፡— ካህናቱ ፡ ሕዝቡን ፡ ለመቀደስ ፡ ወደ ፡ ውጭው ፡ አደባባይ ፡ እንዳያወጡ ፡ የበደሉን ፡ መሥዋዕትና ፡ የኃጢአቱን ፡ መሥዋዕት ፡ የሚቀቅሉበት ፥ የእህሉንም ፡ ቍርባን ፡ የሚጋግሩበት ፡ ስፍራ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አለኝ ።

በውጭው ፡ አደባባይ ፡ አወጣኝ ፡ በአደባባይም ፡ ወዳለው ፡ ወደ ፡ አራቱ ፡ ማዕዘን ፡ አዞረኝ ፤ እነሆም ፥ በአደባባዩ ፡ ማዕዘን ፡ ሁሉ ፡ አደባባይ ፡ ነበረ ። በአደባባዩ ፡ በአራቱ ፡ ማዕዘን ፡ ርዝመቱ ፡ አርባ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ ሠላሳ ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፡ የታጠረ ፡ አደባባይ ፡ ነበረ ፤ በማዕዘኑ ፡ ላሉ ፡ ለእነዚህ ፡ ለአራቱ ፡ ስፍራዎች ፡ አንድ ፡ ልክ ፡ ነበረ ። በአራቱም ፡ ዙሪያ ፡ ሁሉ ፡ ግንብ ፡ ነበረ ፥ በግንቡም ፡ ሥር ፡ በዙሪያው ፡ የመቀቀያ ፡ ቦታ ፡ ነበረ ። እርሱም ፡— እነዚህ ፡ የቤቱ ፡ አገልጋዮች ፡ የሕዝቡን ፡ መሥዋዕት ፡ የሚቀቅሉባቸው ፡ ስፍራዎች ፡ ናቸው ፡ አለኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፯ ።

ወደ ፡ መቅደሱም ፡ መዝጊያ ፡ መለሰኝ ፤ እነሆም ፥ ውኃ ፡ ከቤቱ ፡ መድረክ ፡ በታች ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይወጣ ፡ ነበር ፥ የቤቱ ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይመለከት ፡ ነበርና ፤ ውኃውም ፡ ከቤቱ ፡ ከቀኝ ፡ ወገን ፡ በታች ፡ በመሠዊያው ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ይወርድ ፡ ነበር ። በሰሜኑም ፡ በር ፡ በኩል ፡ አወጣኝ ፤ በስተ ፡ ውጭ ፡ ባለው ፡ መንገድ ፥ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ወደሚመለከት ፡ በስተ ፡ ውጭ ፡ ወዳለው ፡ በር ፡ አዞረኝ ፤ እነሆም ፥ ውኃው ፡ በቀኙ ፡ ወገን ፡ ይፈስስ ፡ ነበር ።

ሰውዬውም ፡ ገመዱን ፡ በእጁ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ወጣ ፡ አንድ ፡ ሺህም ፡ ክንድ ፡ ለካ ፥ በውኃውም ፡ ውስጥ ፡ አሻገረኝ ፥ ውኃም ፡ እስከ ፡ ቍርጭምጭሚት ፡ ደረሰ ። ደግሞ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ ለካ ፡ በውኃውም ፡ ውስጥ ፡ አሻገረኝ ፥ ውኃውም ፡ እስከ ፡ ጕልበት ፡ ደረሰ ። ደግሞ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ ለካ ፡ በውኃውም ፡ ውስጥ ፡

አሻገረኝ ÷ ውኃውም ፡ እስከ ፡ ወገብ ፡ ደረሰ ።
፭ ደግሞ ፡ አንድ ፡ ሺህ ፡ ለካ ፡ ልሻገረውም ፡ የማ
ልችለው ፡ ወንዝ ፡ ሆነ ፤ ውኃውም ፡ ጥልቅ ፡
ነበረ ÷ የሚዋኝበትም ፡ ውኃ ፡ ነበረ ፤ ሰው ፡
ሊሻገረው ፡ የማይችለው ፡ ወንዝ ፡ ነበረ ።
፮ እርሱም ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ አይተሃ
ልን ? አለኝ ። አመጣኝም ÷ ወደ ፡ ወንዙም ፡
፯ ዳር ፡ መለሰኝ ። በተመለስሁም ፡ ጊዜ ÷ እነሆ ÷
በወንዙ ፡ ዳር ፡ በዚህና ፡ በዚያ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡
፰ ዛፎች ፡ ነበሩ ። እርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡—
ይህ ፡ ውኃ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ምድር ፡ ይወጣል ፡
ወደ ፡ ዓረባም ፡ ይወርዳል ፡ ወደ ፡ ባሕሩም ፡
ይገባል ፤ ወደ ፡ ባሕሩም ፡ ወደ ፡ ረከሰው ፡ ውኃ ፡
፱ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ውኃው ፡ ይፈወሳል ። ሕያው ፡
ነፍስ ፡ ያለው ፡ ተንቀሳቃሽ ፡ ሁሉ ፡ ወንዙ ፡
በመጣበት ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ በሕይወት ፡ ይኖ
ራል ፤ ይህም ፡ ውኃ ፡ በዚያ ፡ ስለ ፡ ደረሰ ፡ ዓሣ
ዎች ፡ እጅግ ፡ ይበዛሉ ፤ የባሕሩም ፡ ውኃ ፡ ይፈ
ወሳል ÷ ወንዙም ፡ በሚመጣበት ፡ ያለው ፡
፲ ሁሉ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራል ። አጥማጆችም ፡
በዚያ ፡ ይቆማሉ ፤ ከዓይንጋዲ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ዓይንኤግላይም ፡ ድረስ ፡ መረብ ፡ መዘርጊያ ፡
ይሆናል ፤ ዓሣዎችም ፡ እንደ ፡ ታላቁ ፡ ባሕር ፡
ዓሣዎች ፡ በየወገናቸው ፡ እጅግ ፡ ይበዛሉ ።
፲፩ እረግረጉና ፡ እቋሪው ፡ ውኃ ፡ ግን ፡ ጨው ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ ይኖራል ፡ እንጂ ፡ አይፈወስም ።
፲፪ በወንዙም ፡ አጠገብ ፡ በዳሩ ፡ ላይ ፡ በዚህና ፡
በዚያ ፡ ፍሬው ፡ የሚበላ ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ይበቅ
ላል ÷ ቅጠሉም ፡ አይረግፍም ፡ ፍሬውም ፡ አይ
ጐድልም ፤ ውኃውም ፡ ከመቅደስ ፡ ይወጣልና ፡
በየወሩ ፡ ሁሉ ፡ የፍሬ ፡ በኵር ፡ ያገኛል ፤ ፍሬ
ውም ፡ ለመብል ፡ ቅጠሉም ፡ ለመድኃኒት ፡
ይሆናል ።
፲፫ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡—
ርስት ፡ አድርጋችሁ ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ የእስ
ራኤል ፡ ነገዶች ፡ ምድሪቱን ፡ የምትከፍሉበት ፡
ድንበር ፡ ይህ ፡ ነው ። ለዮሴፍ ፡ ሁለት ፡ እድል ፡
፲፬ ፈንታ ፡ ይሆናል ። ለአባቶቻችሁ ፡ እሰጣቸው ፡
ዘንድ ፡ ምዬ ፡ ነበርና ፡ እናንተ ፡ እኩል ፡ አድር
ጋችሁ ፡ ተካፈሉት ፤ ይህችም ፡ ምድር ፡ ርስት ፡
ትሆናችኋለች ።
፲፭ የምድሪቱም ፡ ድንበር ፡ ይህ ፡ ነው ። በሰ
ሜኑ ፡ ወገን ፡ ከታላቁ ፡ ባሕር ፡ ጀምሮ ፡ በሔት
፲፮ ሎን ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡ ጽዳድ ፡ መግቢያ ፤ ሐማት ÷
ቤሮታ ÷ በደማስቆ ፡ ድንበርና ፡ በሐማት ፡ ድን
በር ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ሲብራይም ÷ በሐው
ራን ፡ ድንበር ፡ አጠገብ ፡ ያለው ፡ ሐጸርሃቲኮን ።
፲፯ ድንበሩ ፡ ከባሕሩ ፡ በደማስቆ ፡ ድንበር ፡ ላይ ፡
ያለው ፡ ሐጸርዔናን ፡ ይሆናል ÷ በሰሜንም ፡
በኩል ፡ የሐማት ፡ ድንበር ፡ አለ ። የሰሜኑ ፡ ድን
፲፰ በር ፡ ይህ ፡ ነው ። የምሥራቁም ፡ ድንበር ፡ በሐ
ውራን ፡ በደማስቆና ፡ በገለዓድ ፡ በእስራኤልም ፡
ምድር ፡ መካከል ፡ ዮርዳኖስ ፡ ይሆናል ። ከሰ
ሜኑ ፡ ድንበር ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምሥራቁ ፡
ባሕር ፡ እስከ ፡ ታማር ፡ ድረስ ፡ የምሥራቁ ፡
፲፱ ድንበር ፡ ይህ ፡ ነው ። የደቡቡም ፡ ድንበር ፡
ከታማር ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሜሪባ ፡ ቃዴስ ፡
ውኃ ፡ እስከ ፡ ግብጽ ፡ ወንዝ ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡
ባሕር ፡ ድረስ ፡ ይሆናል ። የደቡቡ ፡ ድንበር ፡
፳ ይህ ፡ ነው ። የምዕራቡም ፡ ድንበር ፡ ከደቡቡ ፡
ድንበር ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሐማት ፡ መግቢያ ፡
አንጻር ፡ ድረስ ፡ ታላቁ ፡ ባሕር ፡ ይሆናል ። የም
ዕራቡ ፡ ድንበር ፡ ይህ ፡ ነው ።
፳፩ እንዲሁ ፡ ይህችን ፡ ምድር ፡ እንደ ፡ እስራ
ኤል ፡ ነገዶች ፡ መጠን ፡ ለእናንተ ፡ ትካፈላላ
፳፪ ችሁ ። ለእናንተና ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡ ለሚ
ቀመጡ ፡ በእናንተም ፡ መካከል ፡ ልጆችን ፡ ለሚ
ወልዱ ፡ መጻተኞች ፡ ርስት ፡ አድርጋችሁ ፡
በዕጣ ፡ ትካፈሉአታላችሁ ፤ እነርሱም ፡ በእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ እንዳሉ ፡ የአገር ፡
ልጆች ፡ ይሆኑላችኋል ÷ በእስራኤልም ፡ ነገ
ዶች ፡ መካከል ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ርስትን ፡ ይወ
፳፫ ርሳሉ ። መጻተኛውም ፡ በማናቸውም ፡ ነገድ ፡
መካከል ፡ ቢቀመጥ ፡ በዚያ ፡ ርስቱን ፡ ትሰጡታ
ላችሁ ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፰ ።

፩ የነገዶችም ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ። በሔትሎን ፡
መንገድ ፡ አጠገብ ፡ ወደ ፡ ሐማት ፡ መግቢያ ÷
በደማስቆም ፡ ድንበር ፡ ባለው ፡ በሐጸርዔናን ፡
በሐማትም ፡ አጠገብ ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ካለው ፡
ከሰሜን ፡ ድንበር ፡ ይጀምራል ። ወርዳቸ
ውም ፡ ከምሥራቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡
ድረስ ፡ ይሆናል ። ለዳን ፡ አንድ ፡ የዕጣ ፡ ክፍል ፡
፪ ይሆናል ። ከዳንም ፡ ድንበር ፡ ቀጥሎ ፡ ከምሥ
ራቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ድረስ ፡ ለአሴር ፡
፫ አንድ ፡ የዕጣ ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ። ከአሴርም ፡
ድንበር ፡ ቀጥሎ ፡ ከምሥራቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ምዕራብ ፡ ድረስ ፡ ለንፍታሌም ፡ አንድ ፡ የዕጣ ፡
፬ ክፍል ፡ ይሆናል ። ከንፍታሌም ፡ ድንበር ፡
ቀጥሎ ፡ ከምሥራቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡
ድረስ ፡ ለምናሴ ፡ አንድ ፡ የዕጣ ፡ ክፍል ፡ ይሆ
፭ ናል ። ከምናሴም ፡ ድንበር ፡ ቀጥሎ ፡ ከምሥ
ራቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ድረስ ፡ ለኤፍ
፮ ሬም ፡ አንድ ፡ የዕጣ ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ። ከኤፍ
ሬምም ፡ ድንበር ፡ ቀጥሎ ፡ ከምሥራቅ ፡ ጀምሮ ፡
እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ድረስ ፡ ለሮቤል ፡ አንድ ፡
፯ የዕጣ ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ። ከሮቤልም ፡ ድን
በር ፡ ቀጥሎ ፡ ከምሥራቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕ
ራብ ፡ ድረስ ፡ ለይሁዳ ፡ አንድ ፡ የዕጣ ፡ ክፍል ፡
ይሆናል ።
፰ ከይሁዳም ፡ ድንበር ፡ ቀጥሎ ፡ ከምሥራቅ ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ድረስ ፡ ለመባ ፡ የሆነ ፡
የዕጣ ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ፤ ወርዱ ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡
ሺህ ፡ ክንድ ፡ ይሆናል ፡ ርዝመቱም ፡ ከምሥ
ራቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ድረስ ፡ ከዕጣ ፡
ክፍሎች ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ይሆናል ÷ መቅደ
፱ ሱም ፡ በመካከሉ ፡ ይሆናል ። ለእግዚአብሔር ፡

የምታቀርቡት ፡ መባ ፡ ርዝመቱ ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ወርዱም ፡ ሀያ ፡ ሺህ ፡ ክንድ ፡ ይሆናል ።
፲ ለእነዚህም ፡ ለካህናቱ ፡ የተቀደሰ ፡ መባ ፡ ይሆናል ፤ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ርዝመቱ ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ሺህ ÷ በምዕራብም ፡ በኩል ፡ ወርዱ ፡ አሥር ፡ ሺህ ÷ በምሥራቅም ፡ በኩል ፡ ወርዱ ፡ አሥር ፡ ሺህ ÷ በደቡብም ፡ በኩል ፡ ርዝመቱ ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ክንድ ፡ ይሆናል ። የእግዚአብሔርም ፡ መቅደስ ፡ በመካከሉ ፡ ይሆናል ።
፲፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በሳቱ ፡ ጊዜ ÷ ሌዋውያን ፡ እንደ ፡ ሳቱ ፡ ላልሳቱት ፡ ሥርዓቴን ፡ ለጠበቁት ፡ ከሳዶቅ ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ ለተቀደሱት ፡ ካህናት ፡ ይሆናል ።
፲፪ ከምድርም ፡ መባ ፡ የተለየ ፡ መባ ፡ ይሆንላቸዋል ÷ ከሁሉም ፡ ይልቅ ፡ የተቀደሰ ፡ ይሆናል ፤ በሌዋውያን ፡ ድንበር ፡ አጠገብ ፡ ይሆናል ።
፲፫ በካህናቱም ፡ ድንበር ፡ አንጻር ፡ ርዝመቱ ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ወርዱም ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ የሆነ ፡ ዕጣ ፡ ለሌዋውያን ፡ ይሆናል ፤ ርዝመቱ ፡ ሁሉ ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ወርዱም ፡ ሀያ ፡ ሺህ ፡ ክንድ ፡ ይሆናል ።
፲፬ ለእግዚአብሔርም ፡ የተቀደሰ ፡ ነውና ፡ ከእርሱ ፡ ምንም ፡ አይሸጡም ፡ አይለውጡምም ÷ የምድሩም ፡ በኵራት ፡ አይፋለስም ።
፲፭ በሀያ ፡ አምስቱም ፡ ሺህ ፡ አንጻር ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ወርድ ፡ ያለው ፡ የቀረ ፡ ስፍራ ፡ ለከተማይቱ ፡ ለጋራ ፡ ጉዳይዋ ÷ ለመኖሪያ ፡ ለማሰማርያም ፡ ይሆናል ፤ ከተማይቱም ፡ በመካከሉ ፡ ትሆናለች ።
፲፮ ልክዋም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ በሰሜን ፡ በኩል ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ÷ በደቡብም ፡ በኩል ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ÷ በምሥራቅም ፡ በኩል ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ÷ በምዕራብም ፡ በኩል ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ ይሆናል ።
፲፯ ለከተማይቱም ፡ ማሰማርያ ፡ ይኖራታል ፤ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ÷ በደቡብም ፡ በኩል ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ÷ በምሥራቅም ፡ በኩል ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ÷ በምዕራብም ፡ በኩል ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ክንድ ፡ ይሆናል ።
፲፰ በተቀደሰው ፡ መባ ፡ አንጻር ፡ የተረፈው ፡ ርዝመቱ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ወደ ፡ ምዕራብም ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡ ክንድ ፡ ይሆናል ። በተቀደሰው ፡ መባ ፡ አንጻር ፡ ይሆናል ። ፍሬውም ፡ ከተማይቱን ፡ ለሚያገለግሉ ፡ ለመብል ፡ ይሆናል ።
፲፱ ከእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ ከተማይቱን ፡ የሚያገለግሉ ፡ ያርሱታል ።
፳ መባው ፡ ሁሉ ፡ ርዝመቱ ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ወርዱም ፡ ሀያ ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ክንድ ፡ ይሆናል ፤ የተቀደሰውን ፡ መባ ፡ ከከተማይቱ ፡ ይዞታ ፡ ጋር ፡ አራት ፡ ማዕዘን ፡ አድርጋችሁ ፡ ትሰጣላችሁ ።
፳፩ በተቀደሰው ፡ መባና ፡ በከተማይቱ ፡ ይዞታ ፡ በዚህና ፡ በዚያ ፡ ወገን ፡ የቀረው ፡ ለአለቃው ፡ ይሆናል ፤ በመባው ፡ በሀያ ፡ አምስቱ ፡ ሺህ ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ምሥራቁ ፡ ድንበር ÷ በምዕራብም ፡ በኩል ፡ በሀያ ፡ አምስቱ ፡ ሺህ ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ምዕራቡ ፡ ድንበር ÷ እንደ ፡ ዕጣ ፡ ክፍል ፡ ሁሉ ፡ መጠን ÷ ለአለቃው ፡ ይሆናል ፤ የተቀደሰውም ፡ መባና ፡ ቤተ ፡ መቅደሱ ፡ በመካከሉ ፡ ይሆናል ።
፳፪ የሌዋውያንም ፡ ርስት ፡ የከተማይቱም ፡ ይዞታ ፡ ለአለቃው ፡ በሆነው ፡ መካከል ፡ ይሆናል ፤ በይሁዳ ፡ ድንበርና ፡ በብንያም ፡ ድንበር ፡ መካከል ፡ የአለቃ ፡ ዕጣ ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ።
፳፫ ለቀሩትም ፡ ነገዶች ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ፤ ከምሥራቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ድረስ ፡ ለብንያም ፡ አንድ ፡ የዕጣ ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ።
፳፬ ከብንያምም ፡ ድንበር ፡ ቀጥሎ ፡ ከምሥራቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ድረስ ፡ ለስምዖን ፡ አንድ ፡ የዕጣ ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ።
፳፭ ከስምዖንም ፡ ድንበር ፡ ቀጥሎ ፡ ከምሥራቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ድረስ ፡ ለይሳኮር ፡ አንድ ፡ የዕጣ ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ።
፳፮ ከይሳኮርም ፡ ድንበር ፡ ቀጥሎ ፡ ከምሥራቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ድረስ ፡ ለዛብሎን ፡ አንድ ፡ የዕጣ ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ።
፳፯ ከዛብሎንም ፡ ድንበር ፡ ቀጥሎ ፡ ከምሥራቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ድረስ ፡ ለጋድ ፡ አንድ ፡ የዕጣ ፡ ክፍል ፡ ይሆናል ።
፳፰ ከጋድም ፡ ድንበር ፡ ቀጥሎ ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ድንበሩ ፡ ከታማር ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሜሪባ ፡ ቃዴስ ፡ ውኃ ፡ እስከ ፡ ግብጽ ፡ ወንዝ ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፡ ይሆናል ።
፳፱ ርስት ፡ አድርጋችሁ ፡ ለእስራኤል ፡ ነገዶች ፡ በዕጣ ፡ የምታካፍሉአት ፡ ምድር ፡ ይህች ፡ ናት ÷ የእያንዳንዱም ፡ ዕጣ ፡ እንደዚህ ፡ ነው ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።
፴ የከተማይቱም ፡ መውጫዎች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ። በሰሜን ፡ ወገን ፡ ልኩ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡ ነው ።
፴፩ የከተማይቱ ፡ በሮች ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ ነገዶች ፡ ስም ፡ ይሆናሉ ፤ በሰሜን ፡ በኩል ፡ አንዱ ፡ የሮቤል ፡ በር ፡ አንዱም ፡ የይሁዳ ፡ በር ፡ አንዱም ፡ የሌዊ ፡ በር ÷ ሦስት ፡ በሮች ፡ ይሆናሉ ።
፴፪ በምሥራቁም ፡ ወገን ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ÷ ሦስትም ፡ በሮች ፡ አሉ ፤ አንዱ ፡ የዮሴፍ ፡ በር ፡ አንዱም ፡ የብንያም ፡ በር ፡ አንዱም ፡ የዳን ፡ በር ፡ ነው ።
፴፫ በደቡቡም ፡ ወገን ፡ ልኩ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ÷ ሦስትም ፡ በሮች ፡ አሉ ፤ አንዱ ፡ የስምዖን ፡ በር ፡ አንዱም ፡ የይሳኮር ፡ በር ፡ አንዱም ፡ የዛብሎን ፡ በር ፡ ነው ።
፴፬ በምዕራቡም ፡ ወገን ፡ ልኩ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ክንድ ÷ ሦስትም ፡ በሮች ፡ አሉ ፤ አንዱ ፡ የጋድ ፡ በር ፡ አንዱም ፡ የአሴር ፡ በር ፡ አንዱም ፡ የንፍታሌም ፡ በር ፡ ነው ።
፴፭ ዙሪያዋም ፡ አሥራ ፡ ስምንት ፡ ሺህ ፡ ክንድ ፡ ይሆናል ÷ ከዚያም ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ የከተማይቱ ፡ ስም ፡— እግዚአብሔር ፡ በዚያ ፡ አለ ፡ ተብሎ ፡ ይጠራል ።

# ትንቢተ ፡ ዳንኤል ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮአቄም ፡ በነገሠ ፡ በሦስተኛው ፡ ዓመት ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጥቶ ፡ ከበበት ። ፪ ጌታም ፡ የይሁዳን ፡ ንጉሥ ፡ ኢዮአቄምን ፡ ከእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ዕቃ ፡ ከፍሎ ፡ በእጁ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠው ፤ እርሱም ፡ ወደ ፡ ሰናዖር ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ አምላኩ ፡ ቤት ፡ ወሰደው ፥ ዕቃውንም ፡ ወደ ፡ አምላኩ ፡ ግምጃ ፡ ቤት ፡ አገባው ። ፫፡፬ ንጉሡም ፡ ነውር ፡ የሌለባቸውንና ፡ መልከ ፡ መልካሞቹን ፥ በጥበብ ፡ ሁሉ ፡ የሚያስተውሉትን ፡ እውቀትም ፡ የሞላባቸውን ፡ ብልሃተኞችና ፡ አስተዋዮች ፡ የሆኑትን ፥ በንጉሡም ፡ ቤት ፡ መቆም ፡ የሚችሉትን ፡ ብላቴኖች ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከነገሥታቱና ፡ ከመሳፍንቱ ፡ ዘር ፡ ያመጣ ፡ ዘንድ ፡ የከለዳውያንንም ፡ ትምህርትና ፡ ቋንቋ ፡ ያስተምሩአቸው ፡ ዘንድ ፡ ለጃንደረቦች ፡ አለቃ ፡ ለአስፋኔዝ ፡ ነገረ ። ፭ ንጉሡም ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ያሳድጉአቸው ፡ ዘንድ ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ ይቆሙ ፡ ዘንድ ፡ ከንጉሡ ፡ መብል ፡ ከሚጠጣውም ፡ ጠጅ ፡ በየዕለቱ ፡ ድርጎአቸውን ፡ አዘዘላቸው ። ፮ በእነዚህም ፡ መካከል ፡ ከይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ዳንኤልና ፡ አናንያ ፡ ሚሳኤልና ፡ አዛርያ ፡ ነበሩ ። ፯ የጃንደረቦቹም ፡ አለቃ ፡ ስም ፡ አወጣላቸው ፤ ዳንኤልን ፡ ብልጣሶር ፥ አናንያንም ፡ ሲድራቅ ፥ ሚሳኤልንም ፡ ሚሳቅ ፥ አዛርያንም ፡ አብደናጎ ፡ ብሎ ፡ ጠራቸው ።

፰ ዳንኤልም ፡ በንጉሡ ፡ መብልና ፡ በሚጠጣው ፡ ጠጅ ፡ እንዳይረከስ ፡ በልቡ ፡ አሰበ ፤ እንዳይረክስም ፡ የጃንደረቦቹን ፡ አለቃ ፡ ለመነ ። ፱ እግዚአብሔርም ፡ በጃንደረቦቹ ፡ አለቃ ፡ ፊት ፡ ለዳንኤል ፡ ሞገስንና ፡ ምሕረትን ፡ ሰጠው ። ፲ የጃንደረቦቹም ፡ አለቃ ፡ ዳንኤልን ፡— መብሉንና ፡ መጠጡን ፡ ያዘዘላችሁን ፡ ጌታዬን ፡ ንጉሡን ፡ እፈራለሁ ፤ በዕድሜ ፡ እንደ ፡ እናንተ ፡ ካሉ ፡ ብላቴኖች ፡ ይልቅ ፡ ፊታችሁ ፡ ከስቶ ፡ ያየ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ከንጉሡ ፡ ዘንድ ፡ በራሴ ፡ ታስፈርዱብኛላችሁ ፡ አለው ። ፲፩ ዳንኤልም ፡ የጃንደረቦቹ ፡ አለቃ ፡ በዳንኤልና ፡ በአናንያ ፡ በሚሳኤልና ፡ በአዛርያ ፡ ላይ ፡ የሾመውን ፡ ሜልዳርን ፡— ፲፪ እኛን ፡ ባሪያዎችህን ፡ አሥር ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ ትፈትነን ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ፤ የምንበላውንም ፡ ጥራጥሬ ፡ የምንጠጣውንም ፡ ውኃ ፡ ፲፫ ይስጡን ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የእኛን ፡ ፊትና ፡ ከንጉሡ ፡ መብል ፡ የሚበሉትን ፡ የብላቴኖችን ፡ ፊት ፡ ተመልከት ፤ እንዳየኸውም ፡ ሁሉ ፡ ከባሪያዎችህ ፡ ጋር ፡ የወደድኸውን ፡ አድርግ ፡ አለው ።

፲፬ ይህንም ፡ ነገራቸውን ፡ ሰምቶ ፡ አሥር ፡ ቀን ፡ ፈተናቸው ። ፲፭ ከአሥር ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ከንጉሡ ፡ መብል ፡ ከበሉ ፡ ብላቴኖች ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ፊታቸው ፡ አምሮ ፡ ሥጋቸውም ፡ ወፍሮ ፡ ታየ ። ፲፮ ሜልዳርም ፡ መብላቸውንና ፡ የሚጠጡትን ፡ ጠጅ ፡ አስቀርቶ ፡ ጥራጥሬውን ፡ ሰጣቸው ።

፲፯ ለእነዚህም ፡ ለአራቱ ፡ ብላቴኖች ፡ እግዚአብሔር ፡ በትምህርትና ፡ በጥበብ ፡ ሁሉ ፡ እውቀትንና ፡ ማስተዋልን ፡ ሰጣቸው ፤ ዳንኤልም ፡ በራእይና ፡ በሕልም ፡ ሁሉ ፡ አስተዋይ ፡ ነበረ ። ፲፰ እነርሱም ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ ንጉሡ ፡ ያዘዘው ፡ ቀን ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፥ የጃንደረቦቹ ፡ አለቃ ፡ ወደ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ዘንድ ፡ አገባቸው ። ፲፱ ንጉሡም ፡ በተነጋገራቸው ፡ ጊዜ ፡ ከብላቴኖቹ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ዳንኤልና ፡ እንደ ፡ አናንያ ፡ እንደ ፡ ሚሳኤልና ፡ እንደ ፡ አዛርያ ፡ ያለ ፡ አልተገኘም ፤ በንጉሡም ፡ ፊት ፡ ቆሙ ። ፳ ንጉሡም ፡ በጠየቃቸው ፡ በጥበብና ፡ በማስተዋል ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በግዛቱ ፡ ሁሉ ፡ ከሚኖሩ ፡ የሕልም ፡ ተርጓሚዎችና ፡ አስማተኞች ፡ ሁሉ ፡ እነርሱ ፡ አሥር ፡ እጅ ፡ የበለጡ ፡ ሆነው ፡ አገኘባቸው ። ፳፩ ዳንኤልም ፡ እስከ ፡ ንጉሡ ፡ እስከ ፡ ቂሮስ ፡ መጀመርያ ፡ ዓመት ፡ ተቀመጠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ናቡከደነፆርም ፡ በነገሠ ፡ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ ናቡከደነፆር ፡ ሕልም ፡ አለመ ፤ መንፈሱም ፡ ታወከ ፥ እንቅልፉም ፡ ከእርሱ ፡ ራቀ ። ፪ ለንጉሡም ፡ ሕልሙን ፡ እንዲነግሩት ፡ ንጉሡ ፡ የሕልም ፡ ተርጓሚዎቹንና ፡ አስማተኞቹን ፡ መተተኞቹንና ፡ ከለዳውያኑንም ፡ ይጠሩ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ እነርሱም ፡ ገብተው ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ ቆሙ ። ፫ ንጉሡም ፡— ሕልም ፡ አልሜአለሁ ፥ ሕልሙንም ፡ ለማወቅ ፡ መንፈሴ ፡ ታውኮአል ፡ አላቸው ። ፬ ከለዳውያኑም ፡ ንጉሡን ፡ በሶርያ ፡ ቋንቋ ፡— ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ ሺህ ፡ ዓመት ፡ ንገሥ ፤ ለባሪያዎችህ ፡ ሕልምህን ፡ ንገር ፥ እኛም ፡ ፍቺውን ፡ እናሳይሃለን ፡ ብለው ፡ ተናገሩት ። ፭ ንጉሡም ፡ መለሰ ፡ ከለዳውያኑንም ፡— ነገሩ ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ርቆአል ፤ ሕልሙንና ፡ ፍቺውን ፡ ባታስታውቁኝ ፥ ትቈረጣላችሁ ፡ ቤቶቻችሁም ፡ የጉድፍ ፡ መጣያ ፡ ይደረጋሉ ። ፮ ሕልሙንና ፡ ፍቺውን ፡ ግን ፡ ብታሳዩ ፥ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ስጦታና ፡ ዋጋ ፡ ብዙ ፡ ክብርም ፡ ትቀበላላችሁ ፤ ስለዚህም ፡ ሕልሙንና ፡ ፍቺውን ፡ አሳዩኝ ፡ አላቸው ። ፯ ሁለተኛም ፡ ጊዜ ፡ መለሰው ፡— ንጉሡ ፡ ለባሪያዎቹ ፡ ሕልሙን ፡ ይንገር ፥ እኛም ፡ ፍቺውን ፡ እናሳያለን ፡ አሉት ። ፰ ንጉሡ ፡ መልሶ ፡— ነገሩ ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ራቀ ፡ ታውቃላችሁና ፡ ጊዜውን ፡ እንድታስረዝሙ ፡ እኔ ፡ አው-

፱፡ ቃለሁ ። ሕልሙንም ፡ በታስታውቁኝ ፡ አንድ ፡
ፍርድ ፡ አለባችሁ ፤ ጊዜውን ፡ ለማሳለፍ ፡ የሐሰ
ትንና ፡ የተንኰልን ፡ ቃል ፡ ልትነግሩኝ ፡ አዘጋ
ጅታችኋል ፤ ስለዚህ ፡ ሕልሙን ፡ ንገሩኝ ፥ ፍቺ
ውንም ፡ ማሳየት ፡ እንድትችሉ ፡ አውቃለሁ ፡
፲፡ አለ ። ከለዳውያኑም ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ መል
ሰው ፡— የንጉሡን ፡ ነገር ፡ ያሳይ ፡ ዘንድ ፡ የሚ
ችል ፡ ሰው ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የለም ፤ ከነገሥታ
ትም ፡ ታላቅና ፡ ኃይለኛ ፡ የሆነ ፡ እንደዚህ ፡
ያለ ፡ ነገር ፡ የሕልም ፡ ተርጓሚንና ፡ አስማተ
፲፩፡ ኛን ፡ ከለዳዊንም ፡ አልጠየቀም ። ንጉሡም ፡
የሚጠይቀው ፡ ነገር ፡ የቸገረ ፡ ነው ፤ መኖሪያ
ቸው ፡ ከሰው ፡ ጋር ፡ ካልሆነ ፡ ከአማልክት ፡
በቀር ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ የሚያሳየው ፡ ማንም ፡
፲፪፡ የለም ፡ አሉ ። ስለዚህም ፡ ንጉሡ ፡ ተበሳጨ ፡
እጅግም ፡ ተቈጣ ፥ የባቢሎንንም ፡ ጠቢባን ፡
፲፫፡ ሁሉ ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ። ትእዛዝም ፡ ወጣ ፥
ጠቢባንንም ፡ ይገድሉ ፡ ዘንድ ፡ ጀመሩ ፤ ዳንኤ
ልንና ፡ ባልንጀሮቹንም ፡ ይገድሉ ፡ ዘንድ ፡ ፈለ
ጉአቸው ።

፲፬፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ዳንኤል ፡ የባቢሎንን ፡
ጠቢባን ፡ ይገድል ፡ ዘንድ ፡ የወጣውን ፡ የንጉ
ሡን ፡ የዘበኞቹ ፡ አለቃ ፡ አርዮክን ፡ በፈሊጥና ፡
፲፭፡ በማስተዋል ፡ ተናገረው ፤ ለንጉሡም ፡ አለቃ ፡
ለአርዮክ ፡ መልሶ ፡— የንጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ ስለ
ምን ፡ ቸኰለ ? አለው ። አርዮክም ፡ ነገሩን ፡
፲፮፡ ለዳንኤል ፡ አስታወቀው ። ዳንኤልም ፡ ገብቶ ፡
ፍቺውን ፡ ለንጉሡ ፡ የሚያስታውቅበት ፡ ጊዜ ፡
ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡ ንጉሡን ፡ ለመነ ።

፲፯፡፲፰፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ዳንኤል ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ።
ዳንኤልም ፡ ባልንጀሮቹም ፡ ከቀሩት ፡ ከባቢ
ሎን ፡ ጠቢባን ፡ ጋር ፡ እንዳይሞቱ ፡ ስለዚህ ፡
ምሥጢሩ ፡ ምሕረትን ፡ ከሰማይ ፡ አምላክ ፡ ይለ
ምኑ ፡ ዘንድ ፡ ነገሩን ፡ ለባልንጀሮቹ ፡ ለአናን
ያና ፡ ለሚሳኤል ፡ ለአዛርያ ፡ አስታወቃቸው ።

፲፱፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ምሥጢሩ ፡ በሌሊት ፡
ራእይ ፡ ለዳንኤል ፡ ተገለጠለት ፤ ዳንኤልም ፡
፳፡ የሰማይን ፡ አምላክ ፡ አመሰገነ ። ዳንኤልም ፡
ተናገረ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡— ጥበብና ፡ ኃይል ፡
ለእርሱ ፡ ነውና ፡ የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ከዘላ
፳፩፡ ለም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ይባረክ ፤ ጊዜያትንና ፡
ዘመናትን ፡ ይለውጣል ፤ ነገሥታትን ፡ ያፈል
ሳል ፥ ነገሥታትንም ፡ ያስነሣል ፤ ጥበብን ፡ ለጠ
ቢባን ፡ እውቀትንም ፡ ለአስተዋዮች ፡ ይሰጣል ።
፳፪፡ የጠለቀውንና ፡ የተሠወረውን ፡ ይገልጣል ፤
በጨለማ ፡ ያለውን ፡ ያውቃል ፥ ብርሃንም ፡ ከእ
፳፫፡ ርሱ ፡ ጋር ፡ ነው ። ጥበብንና ፡ ኃይልን ፡ የሰጠ
ኸኝ ፥ እኛም ፡ የለመንንህን ፡ ነገር ፡ አሁን ፡ ያስ
ታወቅኸኝ ፥ አንተ ፡ የአባቶቼ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥
የንጉሡን ፡ ነገር ፡ አስታውቀኸኛልና ፡ እገዛል
፳፬፡ ሃለሁ ፡ አመሰግንህማለሁ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡
ዳንኤል ፡ ንጉሡ ፡ የባቢሎንን ፡ ጠቢባን ፡ ያጠፋ ፡
ዘንድ ፡ ወዳዘዘው ፡ ወደ ፡ አርዮክ ፡ ገባ ፤ በገባም ፡
ጊዜ ፡— የባቢሎንን ፡ ጠቢባን ፡ አታጥፋ ፤ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ አስገባኝ ፥ እኔም ፡ ፍቺውን ፡ ለንጉሡ ፡
አሳያለሁ ፡ አለው ።

፳፭፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ አርዮክ ፡ ዳንኤልን ፡ ፈጥኖ ፡
ወደ ፡ ንጉሡ ፡ አስገባውና ፡— ከይሁዳ ፡ ምርኮ
ኞች ፡ ያለውን ፡ ለንጉሡ ፡ ፍቺውን ፡ የሚያስ
ታውቀውን ፡ ሰው ፡ አግኝቼአለሁ ፡ አለው ።
፳፮፡ ንጉሡም ፡ መለሰ ፡ ብልጣሶርም ፡ የሚባለውን ፡
ዳንኤልን ፡— ያየሁትን ፡ ሕልምና ፡ ፍቺውን ፡
ታስታውቀኝ ፡ ዘንድ ፡ ትችላለህን ? አለው ።
፳፯፡ ዳንኤልም ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡
አለ ፡— ንጉሡ ፡ የጠየቀውን ፡ ምሥጢር ፡ ጠቢ
ባንና ፡ አስማተኞች ፡ የሕልም ፡ ተርጓሚዎችና ፡
ቃላተኞች ፡ ለንጉሡ ፡ ያሳዩ ፡ ዘንድ ፡ አይች
፳፰፡ ሉም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ምሥጢር ፡ የሚገልጥ ፡
አምላክ ፡ በሰማይ ፡ ውስጥ ፡ አለ ፥ እርሱም ፡
በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ የሚሆነውን ፡ ለንጉሡ ፡
ለናቡከደነፆር ፡ አስታውቆታል ። በአልጋህ ፡
ላይ ፡ የሆነው ፡ ሕልምና ፡ የራስህ ፡ ራእይ ፡ ይህ ፡
፳፱፡ ነው ። አንተ ፥ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ ከአንተ ፡ በኋላ ፡
የሚሆነው ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በአልጋህ ፡ ላይ ፡
ታስብ ፡ ነበር ፤ ምሥጢርንም ፡ የሚገልጠው ፡
፴፡ የሚሆነውን ፡ ነገር ፡ አስታውቆሃል ። ነገር ፡ ግን ፡
ይህ ፡ ምሥጢር ፡ ለእኔ ፡ መገለጡ ፡ ፍቺው ፡
ለንጉሡ ፡ ይታወቅ ፡ ዘንድ ፥ አንተም ፡ የልብ
ህን ፡ አሳብ ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ካሉ ፡ ሰዎች ፡ ይልቅ ፡ በጥበብ ፡
ስለ ፡ በለጥሁ ፡ አይደለም ።

፴፩፡ አንተ ፥ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ ታላቅ ፡ ምስል ፡
አየህ ፤ ይህም ፡ ምስል ፡ ታላቅና ፡ ብልጭልጭ
ታው ፡ የበዛ ፡ ነበረ ፥ በፊትህም ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፤
፴፪፡ መልኩም ፡ ግሩም ፡ ነበረ ። የዚህም ፡ ምስል ፡
ራስ ፡ ጥሩ ፡ ወርቅ ፥ ደረቱና ፡ ክንዶቹም ፡ ብር ፥
፴፫፡ ሆዱና ፡ ወገቡም ፡ ናስ ፥ ጭኖቹም ፡ ብረት ፥
እግሮቹም ፡ እኩሉ ፡ ብረት ፡ እኩሉም ፡ ሸክላ ፡
፴፬፡ ነበረ ። እጅም ፡ ሳይነካው ፡ ድንጋይ ፡ ከተራ
ራው ፡ ተፈንቅሎ ፡ ከብረትና ፡ ከሸክላ ፡ የሆነ
ውን ፡ የምስሉን ፡ እግሮች ፡ ሲመታና ፡ ሲፈጭ ፡
፴፭፡ አየህ ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ብረቱና ፡ ሸክላው ፥
ናሱና ፡ ብሩ ፡ ወርቁም ፡ በአንድነት ፡ ተፈጨ ፥
በመከርም ፡ ጊዜ ፡ በአውድማ ፡ ላይ ፡ እንዳለ ፡
እብቅ ፡ ሆነ ፤ ነፋስም ፡ ወሰደው ፥ በታውም ፡
አልታወቀም ፤ ምስሉንም ፡ የመታ ፡ ድንጋይ ፡
ታላቅ ፡ ተራራ ፡ ሆነ ፡ ምድርንም ፡ ፈጽሞ ፡
ሞላ ።

፴፮፡ ሕልሙ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ አሁንም ፡ ፍቺውን ፡
፴፯፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ እንናገራለን ። አንተ ፥ ንጉሥ ፡
ሆይ ፥ የሰማይ ፡ አምላክ ፡ መንግሥትንና ፡ ኃይ
ልን ፥ ብርታትንና ፡ ክብርን ፡ የሰጠህ ፡ የነገሥ
፴፰፡ ታት ፡ ንጉሥ ፡ አንተ ፡ ነህ ። በሚቀመጡበ
ትም ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ የሰው ፡ ልጆችንና ፡ የም
ድር ፡ አራዊትን ፡ የሰማይ ፡ ወፎችንም ፡ በእጅህ ፡
አሳልፎ ፡ ሰጥቶሃል ፥ ለሁሉም ፡ ገዥ ፡ አድርጎ
፴፱፡ ሃል ፤ አንተ ፡ የወርቁ ፡ ራስ ፡ ነህ ። ከአንተም ፡
በኋላ ፡ ከአንተ ፡ የሚያንስ ፡ ሌላ ፡ መንግሥት ፡

ይነግሣል ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የሚገዛ ፡ ሌላ ፡ ሦስተኛ ፡ የናስ ፡ መንግሥት ፡ ይነግሣል ። ፵ አራተኛውም ፡ መንግሥት ፡ ሁሉን ፡ እንደሚቀጠቅጥና ፡ እንደሚያደቅቅ ፡ ብረት ፡ ይበረታል ፤ እነዚህንም ፡ ሁሉ ፡ እንደሚፈጭ ፡ ብረት ፡ ይቀጠቅጣል ፡ ይፈጭማል ። ፵፩ እግሮቹና ፡ ጣቶቹም ፡ እኩሉ ፡ ሸክላ ፡ እኩሉም ፡ ብረት ፡ ሆኖ ፡ እንዳየህ ÷ እንዲሁ ፡ የተከፋፈለ ፡ መንግሥት ፡ ይሆናል ፤ ብረቱም ፡ ከሸክላው ፡ ጋር ፡ ተደባልቆ ፡ እንዳየሁ ÷ የብረት ፡ ብርታት ፡ ለእርሱ ፡ ይሆናል ። ፵፪ የእግሮቹም ፡ ጣቶች ፡ እኩሉ ፡ ብረት ፡ እኩሉም ፡ ሸክላ ፡ እንደ ፡ ነበሩ ÷ እንዲሁ ፡ መንግሥቱ ፡ እኩሉ ፡ ብርቱ ፡ እኩሉ ፡ ደካማ ፡ ይሆናል ። ፵፫ ብረቱም ፡ ከሸክላው ፡ ጋር ፡ ተደባልቆ ፡ እንዳየህ ÷ እንዲሁ ፡ ከሰው ፡ ዘር ፡ ጋር ፡ ይደባለቃሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ብረት ፡ ከሸክላ ፡ ጋር ፡ እንደማይጣበቅ ÷ እንዲሁ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ አይጣበቁም ። ፵፬ በእነዚያም ፡ ነገሥታት ፡ ዘመን ፡ የሰማይ ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ፡ የማይፈርስ ፡ መንግሥት ፡ ያስነሣል ፤ ለሌላ ፡ ሕዝብም ፡ የማይሰጥ ፡ መንግሥት ፡ ይሆናል ፤ እነዚያንም ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ ትፈጫቸዋለች ፡ ታጠፋቸውማለች ÷ ለዘላለምም ፡ ትቆማለች ። ፵፭ ድንጋዩም ፡ እጅ ፡ ሳይነካው ፡ ከተራራ ፡ ተፈንቅሎ ፡ ብረቱንና ፡ ናሱን ፡ ሸክላውንና ፡ ብሩን ፡ ወርቁንም ፡ ሲፈጨው ፡ እንዳየህ ÷ እንዲሁ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የሚሆነውን ፡ ታላቁ ፡ አምላክ ፡ ለንጉሡ ፡ አስታውቆታል ፤ ሕልሙም ፡ እውነተኛ ፡ ፍቺውም ፡ የታመነ ፡ ነው ።

፵፮ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ንጉሡ ፡ ናቡከደነፆር ፡ በግምባሩ ፡ ተደፍቶ ፡ ለዳንኤል ፡ ሰገደለት ÷ የእህሉንም ፡ ቍርባን ፡ ዕጣኑንም ፡ ያቀርቡለት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ። ፵፯ ንጉሡም ፡ ዳንኤልን ፡— ይህን ፡ ምሥጢር ፡ ትገልጥ ፡ ዘንድ ፡ ተችሎሃልና ፡ በእውነት ፡ አምላካችሁ ፡ የአማልክት ፡ አምላክ ÷ የነገሥታትም ፡ ጌታ ÷ ምሥጢርም ፡ ገላጭ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ። ፵፰ ንጉሡም ፡ ዳንኤልን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገው ÷ ብዙም ፡ ታላቅ ፡ ስጦታ ፡ ሰጠው ÷ በባቢሎንም ፡ አውራጃ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሾመው ÷ በባቢሎንም ፡ ጠቢባን ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ዋነኛ ፡ አለቃ ፡ አደረገው ። ፵፱ ዳንኤልም ፡ ንጉሡን ፡ ለመነ ÷ እርሱም ፡ ሲድራቅንና ፡ ሚሳቅን ፡ አብደናጎንም ፡ በባቢሎን ፡ አውራጃ ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ ሾማቸው ፤ ዳንኤል ፡ ግን ፡ በንጉሡ ፡ በር ፡ ነበረ ።

ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ንጉሡ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ቁመቱ ፡ ስድሳ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ ስድስት ፡ ክንድ ፡ የሆነውን ፡ የወርቁን ፡ ምስል ፡ አሠራ ፤ በባቢሎንም ፡ አውራጃ ፡ በዱራ ፡ ሜዳ ፡ አቆመው ። ፪ ንጉሡም ፡ ናቡከደነፆር ፡ መኳንንትንና ፡ ሹማምቶችን ÷ አዛገሮችንና ፡ አዛውንቶችን ÷ በጅሮንዶችንና ፡ አማካሪዎችን ÷ መጋቢዎችንም ÷ አውራጃ ፡ ገዦችንም ፡ ሁሉ ፡ ይሰበስቡ ፡ ዘንድ ÷ ንጉሡም ፡ ናቡከደነፆር ፡ ላቆመው ፡ ምስል ፡ ምረቃ ፡ ይመጡ ፡ ዘንድ ፡ ላከ ። ፫ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ መኳንንቱና ፡ ሹማምቶቹ ÷ አዛገሮቹና ፡ አዛውንቶቹ ÷ በጅሮንዶቹና ፡ አማካሪዎቹ ÷ መጋቢዎቹና ፡ አውራጃ ፡ ገዦቹ ፡ ሁሉ ፡ ንጉሡ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ላቆመው ፡ ምስል ፡ ምረቃ ፡ ተሰበሰቡ ፤ ናቡከደነፆርም ፡ ባቆመው ፡ ምስል ፡ ፊት ፡ ቆሙ ። ፬ አዋጅ ፡ ነጋሪውም ፡ እየጮኸ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ወገኖችና ፡ አሕዛብ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ቋንቋም ፡ የምትናገሩ ፡ ሆይ ÷ ፭ የመለከትንና ፡ የእንቢልታን ÷ የመሰንቆንና ፡ የክራርን ÷ የበገናንና ፡ የዋሽንትን ÷ የዘፈንንም ፡ ሁሉ ፡ ድምፅ ፡ በሰማችሁ ፡ ጊዜ ÷ ተደፍታችሁ ፡ ንጉሡ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ላቆመው ፡ ለወርቁ ፡ ምስል ፡ እንድትሰግዱ ፡ ታዝዛችኋል ፤ ፮ ተደፍቶም ፡ የማይሰግድ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በሚነድድ ፡ እሳት ፡ እቶን ፡ ውስጥ ፡ ይጣላል ። ፯ ስለዚህ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ የመለከቱንና ፡ የእንቢልታውን ÷ የመሰንቆውንና ፡ የክራሩን ÷ የበገናውንና ፡ የዘፈኑንም ፡ ሁሉ ፡ ድምፅ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ÷ ወገኖችና ፡ አሕዛብ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ቋንቋም ፡ የተናገሩ ፡ ሁሉ ፡ ተደፉ ÷ ንጉሡም ፡ ናቡከደነፆር ፡ ላቆመው ፡ ለወርቅ ፡ ምስል ፡ ሰገዱ ።

፰ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ከለዳውያን ፡ ቀርበው ፡ አይሁድን ፡ ከሰሱ ። ፱ ለንጉሡም ፡ ለናቡከደነፆር ፡ ተናገሩ ፡ እንዲህም ፡ አሉ ፡— ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ ሺህ ፡ ዓመት ፡ ንገሥ ። ፲ አንተ ÷ ንጉሥ ፡ ሆይ ፡— የመለከትንና ፡ የእንቢልታን ÷ የመሰንቆንና ፡ የክራርን ÷ የበገናንና ፡ የዋሽንትን ÷ የዘፈንንም ፡ ሁሉ ፡ ድምፅ ፡ የሚሰማ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ተደፍቶ ፡ ለወርቁ ፡ ምስል ፡ ይስገድ ፤ ፲፩ ተደፍቶም ፡ የማይሰግድ ፡ በሚነድድ ፡ እሳት ፡ እቶን ፡ ውስጥ ፡ ይጣላል ፡ ብለህ ፡ አዘዝህ ። ፲፪ በባቢሎን ፡ አውራጃ ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ የሾምሃቸው ፡ ሲድራቅና ፡ ሚሳቅ ፡ አብደናጎም ፡ የሚባሉ ፡ አይሁድ ፡ አሉ ፤ ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ትእዛዝህን ፡ እንቢ ፡ ብለዋል ፤ አማልክትህን ፡ አያመልኩም ÷ ላቆምኸውም ፡ ለወርቁ ፡ ምስል ፡ አይሰግዱም ።

፲፫ ናቡከደነፆርም ፡ በብስጭትና ፡ በቍጣ ፡ ሲድራቅንና ፡ ሚሳቅን ፡ አብደናጎንም ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ እነዚህንም ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ፊት ፡ አመጡአቸው ። ፲፬ ናቡከደነፆርም ፡— ሲድራቅና ፡ ሚሳቅ ፡ አብደናጎም ፡ ሆይ ÷ አምላኬን ፡ አለማምለካችሁ ÷ ላቆምሁትም ፡ ለወርቁ ፡ ምስል ፡ አለመስገዳችሁ ፡ እውነት ፡ ነውን ? ፲፭ አሁንም ፡ የመለከቱንና ፡ የእንቢልታውን ፡ የመሰንቆውንና ፡ የክራሩን ፡ የበገናውንና ፡ የዋሽንቱን ፡ የዘፈኑንም ፡ ሁሉ ፡ ድምፅ ፡ በሰማችሁ ፡ ጊዜ ፡ ተደፍታችሁ ፡ ላሠራሁት ፡ ምስል ፡ ብትሰግዱ ፡ መልካም ፡ ነው ፤ ባትሰግዱ ፡ ግን ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ በሚነድድ ፡ እሳት ፡

እቶን ፡ ውስጥ ፡ ትጣላላችሁ ፤ ከእጄስ ፡ የሚያ
ድናችሁ ፡ አምላክ ፡ ማን ፡ ነው ? ብሎ ፡ ተናገራ
፲፮ ቸው ። ሲድራቅና ፡ ሚሳቅ ፡ አብደናጎም ፡
መለሱ ፡ ንጉሡንም ፡— ናቡከደነፆር ፡ ሆይ ÷
በዚህ ፡ ነገር ፡ እንመልስልህ ፡ ዘንድ ፡ አስፈላጊ
፲፯ ያችን ፡ አይደለም ። የምናመልከው ፡ አምላክ
ችን ፡ ከሚነድደው ፡ ከእሳቱ ፡ እቶን ፡ ያድነን ፡
ዘንድ ፡ ይችላል ፤ ከእጅህም ፡ ያድነናል ÷ ንጉሥ ፡
፲፰ ሆይ ! ነገር ፡ ግን ÷ ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ እርሱ ፡ ባያ
ድነን ÷ አማልክትህን ፡ እንዳናመልክ ፡ ላቆም
ኸውም ፡ ለወርቁ ፡ ምስል ፡ እንዳንሰግድለት ፡
እወቅ ፡ አሉት ።

፲፱ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ናቡከደነፆር ፡ በሲድራቅና ፡
በሚሳቅ ፡ በአብደናጎም ፡ ላይ ፡ ቍጣ ፡ ሞላ
በት ÷ የፊቱም ፡ መልክ ፡ ተለወጠባቸው ፤ እር
ሱም ፡ ተናገረ ÷ የእቶንም ፡ እሳት ፡ ይነድድ ፡
ከነበረው ፡ ይልቅ ፡ ሰባት ፡ እጥፍ ፡ አድርገው ፡
፳ እንዲያነድዱት ፡ አዘዘ ። ሲድራቅንና ፡ ሚሳቅ
ንም ፡ አብደናጎንም ፡ ያስሩ ፡ ዘንድ ÷ ወደሚነ
ድድም ፡ ወደ ፡ እቶን ፡ እሳት ፡ ይጥሉአቸው ፡
ዘንድ ፡ በሠራዊቱ ፡ ውስጥ ፡ ከነበሩት ፡ ኃያላን ፡
፳፩ አዘዘ ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ከሰ
ናፊላቸውና ፡ ከቀሚሳቸው ፡ ከመጐናጸፊያቸ
ውም ፡ ከቀረውም ፡ ልብሳቸው ፡ ጋር ፡ ታስ
ረው ፡ በሚነድድ ፡ በእቶን ፡ እሳት ፡ ውስጥ ፡
፳፪ ተጣሉ ። የንጉሡም ፡ ትእዛዝ ፡ አስቸኳይ ፡ ስለ ፡
ሆነ ፡ የእቶኑም ፡ እሳት ፡ እጅግ ፡ ስለሚነድድ ÷
ሲድራቅንና ፡ ሚሳቅን ፡ አብደናጎንም ፡ የጣሉ
አቸውን ፡ ሰዎች ፡ የእሳቱ ፡ ወላፈን ፡ ገደላቸው ።
፳፫ እነዚህም ፡ ሦስቱ ፡ ሰዎች ፡ ሲድራቅና ፡ ሚሳቅ ፡
አብደናጎም ፡ ታስረው ፡ በሚነድደው ፡ በእቶኑ ፡
እሳት ፡ ውስጥ ፡ ወደቁ ።

፳፬ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ንጉሡ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ተደ
ነቀ ፡ ፈጥኖም ፡ ተነሣ ፤ አማካሪዎቹንም ፡— ሦስት ፡
ሰዎች ፡ አስረን ፡ በእሳት ፡ ውስጥ ፡ ጥለን ፡ አል
ነበረምን ? ብሎ ፡ ተናገራቸው ። እነርሱም ፡—
ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ እውነት ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ለን
፳፭ ጉሡ ፡ መለሱለት ። እርሱም ፡— እነሆ ÷ እኔ ፡ የተ
ፈቱ ፡ በእሳቱም ፡ መካከል ፡ የሚመላለሱ ፡
አራት ፡ ሰዎች ፡ አያለሁ ፤ ምንም ፡ አላቈሰላቸ
ውም ፤ የአራተኛውም ፡ መልክ ፡ የአማልክትን ፡
፳፮ ልጅ ፡ ይመስላል ፡ ብሎ ፡ መለሰ ። የዚያን ፡
ጊዜም ፡ ናቡከደነፆር ፡ ወደሚነድደው ፡ ወደ ፡
እሳቱ ፡ እቶን ፡ በር ፡ ቀርቦ ፡— እናንተ ፡ የል
ዑል ፡ አምላክ ፡ ባሪያዎች ÷ ሲድራቅና ፡ ሚሳቅ ፡
አብደናጎም ÷ ኑ ፡ ውጡ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ።
ሲድራቅና ፡ ሚሳቅም ፡ አብደናጎም ፡ ከእሳቱ ፡
፳፯ መካከል ፡ ወጡ ። መሳፍንቱና ፡ ሹማምቶቹም
አዛዦቹና ፡ የንጉሡ ፡ አማካሪዎች ፡ ተሰብስ
በው ፡ እሳቱ ፡ በእነዚያ ፡ ሰዎች ፡ አካል ፡ ላይ ፡
ኃይል ፡ እንዳልነበረው ÷ የራሳቸውም ፡ ጠጕር ፡
እንዳልተቃጠለች ÷ ሰናፊላቸውም ፡ እንዳልተ
ለወጠ ÷ የእሳቱም ፡ ሽታ ፡ እንዳልደረሰባቸው ፡
አዩ ።

፳፰ ናቡከደነፆርም ፡ መለሰ ፡— መልአኩን ፡ የላከ ÷
ከአምላካቸውም ፡ በቀር ፡ ማንንም ፡ አምላክ ፡
እንዳያመልኩ ፡ ለእርሱም ፡ እንዳይሰግዱ ፡ ሰው
ነታቸውን ፡ አሳልፈው ፡ የሰጡትን ፡ የንጉሡ
ንም ፡ ቃል ፡ የተላለፉትን ፡ በእርሱ ፡ የታመኑ
ትን ፡ ባሪያዎቹን ፡ ያዳነ ÷ የሲድራቅና ፡ የሚ
፳፱ ሳቅ ፡ የአብደናጎም ፡ አምላክ ፡ ይባረክ ። እኔም ፡
እንደዚህ ፡ የሚያድን ፡ ሌላ ፡ አምላክ ፡ የለምና ፡
በሲድራቅና ፡ በሚሳቅ ፡ በአብደናጎም ፡ አም
ላክ ፡ ላይ ፡ የስድብን ፡ ነገር ፡ የሚናገር ፡ ወገንና ፡
ሕዝብ ፡ በልዩ ፡ ልዩም ፡ ቋንቋ ፡ የሚናገሩ ፡
ይቈረጣሉ ÷ ቤቶቻቸውም ፡ የጕድፍ ፡ መጣያ ፡
፴ ይደረጋሉ ፡ ብዬ ፡ አዝዣለሁ ፡ አለ ። የዚያን ፡
ጊዜም ፡ ንጉሡ ፡ ሲድራቅንና ፡ ሚሳቅን ፡ አብ
ደናጎንም ፡ በባቢሎን ፡ አውራጃ ፡ ውስጥ ፡
ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጋቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ከንጉሡ ፡ ከናቡከደነፆር ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡
ወደሚቀመጡ ፡ ወገኖችና ፡ አሕዛብ ፡ በልዩ ፡
ልዩ ፡ ቋንቋም ፡ ወደሚናገሩ ፡ ሁሉ ÷ ሰላም ፡
፪ ይብዛላችሁ ። ልዑል ፡ አምላክ ፡ በፊቴ ፡ ያደ
ረገውን ፡ ተአምራቱንና ፡ ድንቁን ፡ አሳያችሁ ፡
፫ ዘንድ ፡ ወድጃለሁ ። ተአምራቱ ፡ እንዴት ፡
ታላቅ ፡ ነው ! ድንቁም ፡ እንዴት ፡ ጽኑ ፡ ነው !
መንግሥቱም ፡ የዘላለም ፡ መንግሥት ፡ ነው ÷
ግዛቱም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ።

፬ እኔ ፡ ናቡከደነፆር ፡ በቤቴ ፡ ደስ ፡ ብሎኝ ፡
፭ በአዳራሼም ፡ ተመችቶኝ ፡ ነበር ። ሕልም ፡
አለምሁ ፤ እርስዋም ፡ አስፈራችኝ ፤ በአልጋ
ዬም ፡ ላይ ፡ የነበረው ፡ አሳቤና ፡ የራሴ ፡ ራእይ ፡
፮ አስጨነቁኝ ። ስለዚህ ፡ የሕልሙን ፡ ፍቺ ፡
እንዲያስታውቁኝ ፡ የባቢሎን ፡ ጠቢባን ፡ ሁሉ ፡
፯ ወደ ፡ እኔ ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ አዘዝሁ ። የዚያን ፡
ጊዜም ፡ የሕልም ፡ ተርጓሚዎቹና ፡ አስማተ
ኞቹ ፡ ከለዳውያኑና ፡ ቃላተኞቹ ፡ ገቡ ፤ ሕልሙ
ንም ፡ በፊታቸው ፡ ተናገርሁ ÷ ፍቺውን ፡ ግን ፡
፰ አላስታወቁኝም ። በመጨረሻም ፡ የቅዱሳን ፡
አማልክት ፡ መንፈስ ፡ ያለበት ፡ እንደ ፡ አምላኬ ፡
ስም ፡ ብልጣሶር ፡ የሚባለው ፡ ዳንኤል ፡ በፊቴ ፡
ገባ ፤ እኔም ፡ ሕልሙን ፡ ነገርሁት ፡ እንዲህም ፡
፱ አልሁት ፡— የሕልም ፡ ተርጓሚዎች ፡ አለቃ ፡
ብልጣሶር ፡ ሆይ ÷ የቅዱሳን ፡ አማልክት ፡ መን
ፈስ ፡ በአንተ ፡ ውስጥ ፡ እንዳለ ÷ ከምሥጢ
ርም ፡ ሁሉ ፡ የሚያስቸግርህ ፡ እንደሌለ ፡ አው
ቄአለሁና ፡ ያለምሁትን ፡ የሕልሜን ፡ ራእይ ፡
፲ ፍቺውንም ፡ ንገረኝ ። የራሴ ፡ ራእይ ፡ በአል
ጋዬ ፡ ላይ ፡ ይህ ፡ ነበረ ፤ እነሆ ÷ በምድር ፡ መካ
ከል ፡ ዛፍ ፡ አየሁ ÷ ቁመቱም ፡ እጅግ ፡ረጅም ፡
፲፩ ነበረ ። ዛፉም ፡ ትልቅ ፡ ሆነ ÷ በረታም ÷ ቁመ
ቱም ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ደረሰ ÷ መልኩም ፡ እስከ ፡
፲፪ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ታየ ። ቅጠሉም ።
የተዋበ ፡ ነበረ ፡ ፍሬውም ፡ ብዙ ፡ ነበረ ÷ ለሁ
ሉም ፡ መብል ፡ ነበረበት ፤ ከጥላውም ፡ በታች ፡

የምድር ፡ አራዊት ፡ ያርፉበት ፡ ነበር ፥ በቅርን
ጫፎቹም ፡ ውስጥ ፡ የሰማይ ፡ ወፎች ፡ ይቀ
መጡ ፡ ነበር ፥ ሥጋ ፡ ለባሹም ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡
፲፫ ይበላ ፡ ነበር ። በአልጋዬም ፡ ላይ ፡ በራሴ ፡
ራእይ ፡ አየሁ ፤ እነሆም ፥ አንድ ፡ ቅዱስ ፡ ጠባቂ ፡
፲፬ ከሰማይ ፡ ወረደ ። በታላቅ ፡ ድምፅም ፡ እየ
ጮኸ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ዛፉን ፡ ቍረጡ ፥ ቅር
ንጫፎቹንም ፡ ጨፍጭፉ ፥ ቅጠሎቹንም ፡ አራ
ግፉ ፥ ፍሬውንም ፡ በትኑ ፤ አራዊትም ፡ ከበ
፲፭ ታቹ ፡ ወፎቹም ፡ ከቅርንጫፉ ፡ ይሽሹ ። ነገር ፡
ግን ፡ ጉቶውን ፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡ ተዉት ፥
በመስክም ፡ ውስጥ ፡ በብረትና ፡ በናስ ፡ ማሰሪያ ፡
ታስሮ ፡ ይቈይ ፤ በሰማይም ፡ ጠል ፡ ይረስርስ ፡
እድል ፡ ፈንታውም ፡ በምድር ፡ ሣር ፡ ውስጥ ፡
፲፮ ከአራዊት ፡ ጋር ፡ ይሁን ። ልቡም ፡ ከሰው ፡
ልብ ፡ ይለወጥ ፥ የአውሬም ፡ ልብ ፡ ይሰጠው ፤
፲፯ ሰባት ፡ ዘመናትም ፡ ይለፉበት ። ልዑሉ ፡ በሰ
ዎች ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ እንዲሠለጥን ፥ ለወደ
ደውም ፡ እንዲሰጠው ፥ ከሰውም ፡ የተዋረደ
ውን ፡ እንዲሾምበት ፡ ሕያዋን ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡
ይህ ፡ ነገር ፡ የጠባቂዎች ፡ ትእዛዝ ፥ ይህም ፡
፲፰ ፍርድ ፡ የቅዱሳን ፡ ቃል ፡ ነው ። እኔ ፡ ንጉሡ ፡
ናቡከደነፆር ፡ ይህን ፡ ሕልም ፡ አልሚአለሁ ፤
አንተም ፥ ብልጣሶር ፥ ፍቺውን ፡ አስታውቀኝ ፥
የመንግሥቴ ፡ ጠቢባን ፡ ሁሉ ፡ ፍቺውን ፡ ያስታ
ውቁኝ ፡ ዘንድ ፡ አይችሉምና ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የቅ
ዱሳን ፡ አማልክት ፡ መንፈስ ፡ በአንተ ፡ ውስጥ ፡
አለና ፡ አንተ ፡ ትችላለህ ።

፲፱ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ብልጣሶር ፡ የተባለው ፡ ዳን
ኤል ፡ አንድ ፡ ሰዓት ፡ ያህል ፡ አሰበ ፥ ልቡም ፡
ታወከ ። ንጉሡም ፡ መልሶ ፡— ብልጣሶር ፡ ሆይ ፥
ሕልሙና ፡ ፍቺው ፡ አያስቸግርህ ፡ አለው ።
ብልጣሶርም ፡ መልሶ ፡ አለ ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥
ሕልሙ ፡ ለሚጠሉህ ፥ ፍቺውም ፡ ለጠላቶችህ ፡
፳ ይሁን ። ትልቅ ፡ የነበረው ፡ የበረታውም ፥ ቁመ
ቱም ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ የደረሰው ፥ መልኩም ፡
፳፩ እስከ ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ድረስ ፡ የታየው ፥ ቅጠ
ሉም ፡ አምሮ ፡ የነበረው ፥ ፍሬውም ፡ የበዛው ፥
ለሁሉም ፡ መብል ፡ የነበረበት ፤ በበታቹም ፡
የምድር ፡ አራዊት ፡ የተቀመጡ ፥ በቅርንጫፎ
ቹም ፡ የሰማይ ፡ ወፎች ፡ ያደሩበት ፡ ያየኸው ፡
፳፪ ዛፍ ፤ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ እርሱ ፡ ታላቅና ፡ ብርቱ ፡
የሆንህ ፡ አንተ ፡ ነህ ፤ ታላቅነትህ ፡ በዝቶአል ፥
እስከ ፡ ሰማይም ፡ ደርሶአል ፥ ግዛትህም ፡ እስከ ፡
፳፫ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ነው ። ንጉሡም ፡ ከሰ
ማይ ፡ የወረደውንና ፡— ዛፉን ፡ ቍረጡ ፥ አጥ
ፉትም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ጉቶውን ፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡
ተዉት ፤ በብረትና ፡ በናስ ፡ ማሰሪያ ፡ ታስሮ ፡
በመስክ ፡ ውስጥ ፡ ይቈይ ፤ በሰማይም ፡ ጠል ፡
ይረስርስ ፥ ሰባት ፡ ዘመናትም ፡ እስኪያልፉበት ፡
ድረስ ፡ እድል ፡ ፈንታው ፡ ከምድር ፡ አራዊት ፡
ጋር ፡ ይሁን ፡ ያለውን ፡ ቅዱስ ፡ ጠባቂ ፡ ማየቱ ፤
፳፬ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ ፍቺው ፡ ይህ ፡ ነው ፤ በጌታዬ ፡
በንጉሥ ፡ ላይ ፡ የወረደው ፡ የልዑሉ ፡ ትእዛዝ ፡
ነው ፤ ልዑሉም ፡ በሰዎች ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ ፳፭
እንዲሠለጥን ፥ ለሚወድደውም ፡ እንዲሰጠው ፡
እስክታውቅ ፡ ድረስ ፡ ከሰዎች ፡ ተለይተህ ፡
ትሰደዳለህ ፥ መኖሪያህም ፡ ከምድር ፡ አራ
ዊት ፡ ጋር ፡ ይሆናል ፥ እንደ ፡ በሬም ፡ ሣር ፡
ትበላ ፡ ዘንድ ፡ ትገደዳለህ ፥ በሰማይም ፡ ጠል ፡
ትረሰርሳለህ ፥ ሰባት ፡ ዘመናትም ፡ ያልፉብሃል ።
፳፮ የዛፉንም ፡ ጉቶ ፡ ይተዉት ፡ ዘንድ ፡ ማዘዙ ፥
ሥልጣን ፡ ከሰማያት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ካወቅህ ፡
፳፯ በኋላ ፡ መንግሥትህ ፡ ይቆይልሃል ። ንጉሥ ፡
ሆይ ፥ ስለዚህ ፡ ምናልባት ፡ የደኅንነትህ ፡ ዘመን ፡
ይረዝም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ምክሬ ፡ ደስ ፡ ያሰኝህ ፤
ኃጢአትህንም ፡ በጽድቅ ፥ በደልህንም ፡ ለድ
ሆች ፡ በመመጽወት ፡ አስቀር ።

፳፰ ይህ ፡ ሁሉ ፡ በንጉሡ ፡ በናቡከደነፆር ፡ ላይ ፡
፳፱ ደረሰ ። ከአሥራ ፡ ሁለት ፡ ወር ፡ በኋላ ፡ በባቢ
ሎን ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ሰገነት ፡ ላይ ፡ ይመላ
፴ ለስ ፡ ነበር ። ንጉሡም ፡— ይህች ፡ እኔ ፡ በጉል
በቴ ፡ ብርታት ፡ ለግርማዬ ፡ ክብር ፡ የመንግ
ሥት ፡ መኖሪያ ፡ እንድትሆን ፡ ያሠራኋት ፡ ታላ
ቂቱ ፡ ባቢሎን ፡ አይደለችምን ? ብሎ ፡ ተናገረ ።
፴፩ ቃሉም ፡ ገና ፡ በንጉሡ ፡ አፍ ፡ ሳለ ፡ ድምፅ ፡
ከሰማይ ፡ ወደቀና ፡— ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡
ሆይ ፡— መንግሥት ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ አለፈች ፡
፴፪ ተብሎ ፡ ለአንተ ፡ ተነግሮአል ፤ ልዑሉም ፡ በሰ
ዎች ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ እንዲሠለጥን ፥ ለሚወ
ድደውም ፡ እንዲሰጠው ፡ እስክታውቅ ፡ ድረስ ፡
ከሰዎች ፡ ተለይተህ ፡ ትሰደዳለህ ፥ መኖሪያ
ህም ፡ ከምድር ፡ አራዊት ፡ ጋር ፡ ይሆናል ፤
እንደ ፡ በሬም ፡ ሣር ፡ ትበላ ፡ ዘንድ ፡ ትገደዳ
ለህ ፥ ሰባት ፡ ዘመናትም ፡ ያልፉብሃል ፡ አለው ።
፴፫ በዚያም ፡ ሰዓት ፡ ነገሩ ፡ በናቡከደነፆር ፡ ላይ ፡
ደረሰ ፤ ጠጕሩም ፡ እንደ ፡ ንስር ፥ ጥፍሩም ፡
እንደ ፡ ወፎች ፡ እስኪረዝም ፡ ድረስ ፡ ከሰዎች ፡
ተለይቶ ፡ ተሰደደ ፥ እንደ ፡ በሬም ፡ ሣር ፡ በላ ፥
አካሉም ፡ በሰማይ ፡ ጠል ፡ ረሰረሰ ።

፴፬ ዘመኑም ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ እኔ ፡ ናቡከደ
ነፆር ፡ ዓይኔን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አነሣሁ ፥ አእም
ሮዬም ፡ ተመለሰልኝ ፤ ልዑሉንም ፡ ባረክሁ ፥
ለዘላለምም ፡ የሚኖረውን ፡ አመሰገንሁ ፡ አከበር
ሁትም ፤ ግዛቱ ፡ የዘላለም ፡ ግዛት ፡ ነውና ፥ መን
፴፭ ግሥቱም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነውና ። በምድርም ፡
የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ምናምን ፡ ይቈጠራሉ ፤
በሰማይም ፡ ሠራዊት ፡ በምድርም ፡ ላይ ፡ በሚ
ኖሩ ፡ መካከል ፡ እንደ ፡ ፈቃዱ ፡ ያደርጋል ፤
እጁንም ፡ የሚከለክላት ፡ ወይም ፡— ምን ፡ ታደ
፴፮ ርጋለህ ? የሚለው ፡ የለም ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡
አእምሮዬ ፡ ተመለሰልኝ ፥ ለመንግሥቴም ፡
ክብር ፡ ግርማዬና ፡ ውበቴ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ተመ
ለሰ ፤ አማካሪዎቼና ፡ መኳንንቶቼም ፡ ፈለጉኝ ፥
በመንግሥቴም ፡ ውስጥ ፡ ጸናሁ ፥ ብዙም ፡
፴፯ ክብር ፡ ተጨመረልኝ ። አሁንም ፡ እኔ ፡ ናቡከ
ደነፆር ፡ የሰማይን ፡ ንጉሥ ፡ አመሰግናለሁ ፥
ታላቅም ፡ አደርገዋለሁ ፥ አከብረውማለሁ ።

በእጁ ፡ የያዘውን ፡ አምላክ ፡ አላከበርኸውም ።
፳፬ ስለዚህም ፡ እነዚህ ፡ የእጅ ፡ ጣቶች ፡ ከእርሱ ፡
ዘንድ ፡ ተልከዋል ፤ ይህም ፡ ጽሕፈት ፡ ተጽፎአል ።
፳፭ የተጻፈውም ፡ ጽሕፈት ፡— ማኔ ፡ ቴቄል ፡
፳፮ ፋሬስ ፡ ይላል ። የነገሩም ፡ ፍቺ ፡ ይህ ፡ ነው ፤
ማኔ ፡ ማለት ÷ እግዚአብሔር ፡ መንግሥትህን ፡
፳፯ ቈጠረው ፡ ፈጸመውም ፡ ማለት ፡ ነው ። ቴቄል ፡
ማለት ÷ በሚዛን ፡ ተመዘንህ ÷ ቀልለህም ፡ ተገ
፳፰ ኘህ ፡ ማለት ፡ ነው ። ፋሬስ ፡ ማለት ÷ መንግ
ሥትህ ፡ ተከፈለ ÷ ለሜዶንና ፡ ለፋርስ ፡ ሰዎ
ችም ፡ ተሰጠ ፡ ማለት ፡ ነው ።

፳፱ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ብልጣሶር ፡ ለዳንኤል ፡ ሐም
ራዊ ፡ ግምጃ ፡ እንዲያለብሱት ÷ የወርቅ ፡ ማር
ዳም ፡ በአንገቱ ፡ ዙሪያ ፡ እንዲያደርጉለት ፡ አዘዘ ፤
በመንግሥትም ፡ ላይ ፡ ሦስተኛ ፡ ገዥ ፡ እንዲ
ሆን ፡ አዋጅ ፡ አስነገረ ።

፴ በዚያ ፡ ሌሊት ፡ የከለዳውያን ፡ ንጉሥ ፡ ብልጣ
፴፩ ሶር ፡ ተገደለ ። ሜዶናዊውም ፡ ዳርዮስ ፡ መን
ግሥቱን ፡ ወሰደ ፤ ዕድሜውም ፡ ስድሳ ፡ ሁለት ፡
ዓመት ፡ ነበረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ዳርዮስም ፡ በመንግሥቱ ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ እን
ዲሆኑ ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ መሳፍንት ፡ በመንግሥቱ ፡
፪ ላይ ፡ ይሾም ፡ ዘንድ ፡ ወደደ ። መሳፍንቱም ፡
ሒሳቡን ፡ ያመጡላቸው ፡ ዘንድ ÷ ንጉሡም ፡
እንዳይጐዳ ፡ ሦስት ፡ አለቆች ፡ በላያቸው ፡ አደ
ረገ ፤ ከእነርሱም ፡ አንደኛው ፡ ዳንኤል ፡ ነበረ ።
፫ ዳንኤልም ፡ መልካም ፡ መንፈስ ፡ ስላለው ፡ ከአ
ለቆችና ፡ ከመሳፍንት ፡ በለጠ ፤ ንጉሡም ፡ በመ
ንግሥቱ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ይሾመው ፡ ዘንድ ፡ አሰበ ።
፬ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ አለቆችና ፡ መሳፍንቱ ፡
ስለ ፡ መንግሥቱ ፡ በዳንኤል ፡ ላይ ፡ ሰበብ ፡ ይፈ
ልጉ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የታመነ ፡ ነበረና ÷ ስሕ
ተትና ፡ በደልም ፡ አልተገኘበትምና ፡ በእርሱ ፡
ላይ ፡ ሰበብና ፡ በደል ፡ ያገኙበት ፡ ዘንድ ፡ አል
፭ ቻሉም ። እነዚያም ፡ ሰዎች ፡— ከአምላኩ ፡
ሕግ ፡ በቀር ፡ በዚህ ፡ በዳንኤል ፡ ላይ ፡ ሌላ ፡
፮ ሰበብ ፡ አናገኝበትም ፡ አሉ ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡
አለቆቹና ፡ መሳፍንቱ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ተሰ
ብስበው ፡ እንዲህ ፡ አሉት ፡— ንጉሥ ፡ ዳር
፯ ዮስ ፡ ሆይ ÷ ሺህ ፡ ዓመት ፡ ንገሥ ። የመንግ
ሥቱ ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ሹማምቶችና ፡ መሳፍ
ንት ፡ አማካሪዎችና ፡ አዛገሮች ፡— ንጉሥ ፡
ሆይ ÷ ከአንተ ፡ በቀር ፡ ማንም ፡ እስከ ፡ ሠላሳ ፡
ቀን ፡ ድረስ ፡ ልመና ፡ ከአምላክ ፡ ወይም ፡
ከሰው ፡ ቢለምን ÷ በአንበሶች ፡ ጕድጓድ ፡
ውስጥ ፡ ይጣል ፡ የሚል ፡ የንጉሥ ፡ ሕግና ፡
ብርቱ ፡ ትእዛዝ ፡ ይወጣ ፡ ዘንድ ፡ ተማከሩ ።
፰ አሁንም ÷ ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ እንደማይለወጠው ፡
እንደ ፡ ሜዶንና ፡ እንደ ፡ ፋርስ ፡ ሕግ ÷ እንዳይ
ለወጥ ፡ ትእዛዙን ፡ አጽና ÷ ጽሕፈቱንም ፡ ጻፍ ።
፱ ንጉሡም ፡ ዳርዮስ ፡ ጽሕፈቱንና ፡ ትእዛዙን ፡ ጻፈ ።
፲ ዳንኤልም ፡ ጽሕፈቱ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ በወቀ ፡
ጊዜ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ገባ ፤ የእልፍኙም ፡ መስኮ
ቶች ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ አንጻር ፡ ተከፍተው ፡
ነበር ፤ ቀድሞም ፡ ያደርግ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ በየ
ዕለቱ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ በጕልበቱ ፡ ተንበርክኮ ፡
፲፩ በአምላኩ ፡ ፊት ፡ ጸለየ ፡ አመሰገነም ። እነዚ
ያም ፡ ሰዎች ፡ ተሰብስበው ፡ ዳንኤል ፡ በአም
ላኩ ፡ ፊት ፡ ሲጸልይና ፡ ሲለምን ፡ አገኙት ።
፲፪ ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ቀርበው ፡ ስለ ፡ ንጉሡ ፡ ትእ
ዛዝ ፡— ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ ከአንተ ፡ በቀር ፡ እስከ ፡
ሠላሳ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ከአምላክ ፡ ወይም ፡ ከሰው ፡
የሚለምን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በአንበሶች ፡ ጕድጓድ ፡
ውስጥ ፡ እንዲጣል ፡ ትእዛዝ ፡ አልጻፍህምን ?
አሉት ። ንጉሡም ፡ መልሶ ፡— ነገሩ ፡ እንደማ
ይለወጠው ፡ እንደ ፡ ሜዶንና ፡ እንደ ፡ ፋርስ ፡
፲፫ ሕግ ፡ እውነት ፡ ነው ፡ አላቸው ። የዚያን ፡
ጊዜም ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ መልሰው ፡— ንጉሥ ፡
ሆይ ÷ ከይሁዳ ፡ ምርኮኞች ፡ የሆነው ፡ ዳንኤል ፡
በየዕለቱ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ልመናውን ፡ ይለም
ናል ፡ እንጂ ፡ አንተንና ፡ የጻፍኸውን ፡ ትእዛዝ ፡
፲፬ አይቀበልም ፡ አሉት ። ንጉሡም ፡ ይህን ፡ ቃል ፡
በሰማ ፡ ጊዜ ፡ በጣም ፡ አዘነ ÷ ያድነውም ፡ ዘንድ ፡
ልቡን ፡ ወደ ፡ ዳንኤል ፡ አደረገ ፤ ሊያድነውም ፡
፲፭ ፀሐይ ፡ እስኪገባ ፡ ድረስ ፡ ደከመ ። የዚያን ፡
ጊዜም ፡ እነዚያ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ተሰብ
ስበው ፡ ንጉሡን ፡— ንጉሥ ፡ ሆይ ÷ ንጉሡ ፡
ያጸናው ፡ ትእዛዝ ፡ ወይም ፡ ሥርዓት ፡ ይለወጥ ፡
ዘንድ ፡ እንዳይገባ ፡ የሜዶንና ፡ የፋርስ ፡ ሕግ ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ እወቅ ፡ አሉት ።

፲፮ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ንጉሡ ፡ አዘዘ ÷ ዳንኤል
ንም ፡ አምጥተው ፡ በአንበሶች ፡ ጕድጓድ ፡
ጣሉት ፤ ንጉሡም ፡ ተናገረ ፡ ዳንኤልንም ፡—
ሁልጊዜ ፡ የምታመልከው ፡ አምላክህ ፡ እርሱ ፡
፲፯ ያድንህ ፡ አለው ። ድንጋይም ፡ አምጥተው ፡
በጕድጓዱ ፡ አፍ ፡ ላይ ፡ ገጠሙበት ፤ ንጉሡም ፡
በዳንኤል ፡ ላይ ፡ የተደረገው ፡ እንዳይለወጥ ፡
በቀለበቱና ፡ በመኳንንቱ ፡ ቀለበት ፡ አተመው ።
፲፰ ንጉሡም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ፡ ሳይበላም ፡ አደረ ፤
መብልም ፡ አላመጡለትም ÷ እንቅልፉም ፡ ከእ
ርሱ ፡ ራቀ ።

፲፱ በነጋውም ፡ ንጉሡ ፡ ማልዶ ፡ ተነሣ ÷ ፈጥ
፳ ኖም ፡ ወደ ፡ አንበሶች ፡ ጕድጓድ ፡ ሄደ ። ወደ ፡
ጕድጓዱም ፡ ወደ ፡ ዳንኤል ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፡
በኀዘን ፡ ቃል ፡ ጠራው ፤ ንጉሡም ፡ ተናገረ ፡
ዳንኤልንም ፡— የሕያው ፡ አምላክ ፡ ባሪያ ፡ ዳን
ኤል ፡ ሆይ ÷ ሁልጊዜ ፡ የምታመልከው ፡ አምላ
ክህ ፡ ከአንበሶች ፡ ያድንህ ፡ ዘንድ ፡ ችሎአልን ?
፳፩ አለው ። ዳንኤልም ፡ ንጉሡን ፡— ንጉሥ ፡ ሆይ ÷
፳፪ ሺህ ፡ ዓመት ፡ ንገሥ ። በፊቱ ፡ ቅንነት ፡ ተገኝ
ቶብኛልና ÷ በአንተም ፡ ፊት ፡ ደግሞ ÷ ንጉሥ ፡
ሆይ ÷ አልበደልሁምና ፡ አምላኬ ፡ መልአኩን ፡
ልኮ ፡ የአንበሶችን ፡ አፍ ፡ ዘጋ ÷ እነርሱም ፡ አል
፳፫ ጐዱኝም ፡ አለው ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ንጉሡ ፡
እጅግ ፡ ደስ ፡ አለው ÷ ዳንኤልንም ፡ ከጕድ
ጓዱ ፡ ያወጡት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ ዳንኤልም ፡

ከጕድጓድ ፡ ወጣ ፥ በአምላኩም ፡ ታምኖ ፡ ነበ
ርና ፡ አንዳች ፡ ጉዳት ፡ አልተገኘበትም ።
፳፬፤ ንጉሡም ፡ አዘዘ ፥ ዳንኤልንም ፡ የከሰሱ ፡
እነዚያን ፡ ሰዎች ፡ አመጡአቸው ፥ እነርሱንና ፡
ልጆቻቸውንም ፡ ሚስቶቻቸውንም ፡ በአንበ
ሶች ፡ ጕድጓድ ፡ ጣሉአቸው ፤ ወደ ፡ ጕድጓ
ዱም ፡ መጨረሻ ፡ ሳይደርሱ ፡ አንበሶች ፡ ያዙአ
ቸው ፡ አጥንታቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ሰበበሩ ።
፳፭፤ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ንጉሥ ፡ ዳርዮስ ፡ በም
ድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ወደሚኖሩ ፡ ወገኖችና ፡ አሕ
ዛብ ፡ በልዩ ፡ ልዩም ፡ ቋንቋ ፡ ወደሚናገሩ ፡
ሁሉ ፡ ጻፈ ፥ እንዲህም ፡ አለ ፡— ሰላም ፡ ይብ
፳፮፤ ዛላችሁ ። በመንግሥቴ ፡ ግዛት ፡ ሁሉ ፡ ያሉ ፡
ሰዎች ፡ በዳንኤል ፡ አምላክ ፡ ፊት ፡ እንዲፈ
ሩና ፡ እንዲንቀጠቀጡ ፡ አዝዣለሁ ፤ እርሱ ፡
ሕያው ፡ አምላክ ፡ ለዘላለም ፡ የሚኖር ፡ ነውና ፤
መንግሥቱም ፡ የማይጠፋ ፡ ነው ፥ ግዛቱም ፡
፳፯፤ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ድረስ ፡ ይኖራል ። ያድናል ፡
ይታደግማል ፥ በሰማይና ፡ በምድርም ፡ ተአ
ምራትንና ፡ ድንቅን ፡ ይሠራል ፥ ዳንኤልንም ፡
ከአንበሶች ፡ አፍ ፡ አድኖታል ።
፳፰፤ ይህም ፡ ዳንኤል ፡ በዳርዮስ ፡ መንግሥትና ፡
በፋርሳዊው ፡ በቂሮስ ፡ መንግሥት ፡ ኑሮው ፡
ተቃናለት ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩፤ በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ በብልጣሶር ፡ በመጀመ
ሪያው ፡ ዓመት ፡ ዳንኤል ፡ በአልጋው ፡ ላይ ፡
ሕልምንና ፡ የራሱን ፡ ራእይ ፡ አየ ፤ ከዚያም ፡
በኋላ ፡ ሕልሙን ፡ ጻፈ ፥ ዋነኛውንም ፡ ነገር ፡
፪፤ ተናገረ ። ዳንኤልም ፡ ተናገረ ፡ እንዲህም ፡
አለ ፡— በሌሊት ፡ በራእይ ፡ አየሁ ፤ እነሆም ፥
አራቱ ፡ የሰማይ ፡ ነፋሳት ፡ በታላቁ ፡ ባሕር ፡
፫፤ ላይ ፡ ይጋጩ ፡ ነበር ። አራትም ፡ ታላላቅ ፡ አራ
ዊት ፡ ከባሕር ፡ ወጡ ፥ እያንዳንዲቱም ፡ ልዩ ፡
፬፤ ልዩ ፡ ነበረች ። መጀመሪያይቱ ፡ አንበሳ ፡
ትመስል ፡ ነበር ፥ የንስርም ፡ ክንፍ ፡ ነበራት ፤
ክንፎችዋም ፡ ከእርስዋ ፡ እስኪነቀሉ ፡ ድረስ ፡
አይ ፡ ነበር ፥ ከምድርም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ተደረ
ገች ፥ እንደ ፡ ሰውም ፡ በሁለት ፡ እግር ፡ እንድ
ትቆም ፡ ተደረገች ፥ የሰውም ፡ ልብ ፡ ተሰጣት ።
፭፤ እነሆም ፥ ሁለተኛይቱ ፡ ድብ ፡ የምትመስል ፡
ሌላ ፡ አውሬ ፡ ነበረች ፥ በአንድ ፡ ወገንም ፡
ቆመች ፥ ሦስትም ፡ የጎድን ፡ አጥንቶች ፡ በአ
ፍዋ ፡ ውስጥ ፡ በጥርስዋ ፡ መካከል ፡ ነበሩ ፤ እን
ደዚህም ፡— ተነሥተሽ ፡ እጅግ ፡ ሥጋ ፡ ብዪ ፡
፮፤ ተባለላት ። ከዚህም ፡ በኋላ ፥ እነሆ ፥ ነብር ፡ የምት
መስል ፡ በጀርባዋም ፡ ላይ ፡ አራት ፡ የወፍ ፡ ክን
ፎች ፡ የነበሩአት ፡ ሌላ ፡ አውሬ ፡ አየሁ ፤ ለአ
ውሬይቱም ፡ አራት ፡ ራሶች ፡ ነበሩአት ፥ ግዛ
፯፤ ትም ፡ ተሰጣት ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በሌሊት ፡
ራእይ ፡ አየሁ ፤ እነሆም ፥ የምታስፈራና ፡ የምታ
ስደነግጥ ፡ እጅግም ፡ የበረታች ፥ ታላላቅም ፡
የብረት ፡ ጥርሶች ፡ የነበሩአት ፡ አራተኛ ፡ አውሬ ፡
ነበረች ፤ ትበላና ፡ ታደቅቅ ፡ ነበር ፥ የቀረው
ንም ፡ በእግርዋ ፡ ትረግጥ ፡ ነበር ፤ ከእርስዋም ፡
በፊት ፡ ከነበሩት ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ፡ የተለየች ፡
፰፤ ነበረች ፤ አሥር ፡ ቀንዶችም ፡ ነበሩአት ። ቀንዶ
ችንም ፡ ተመለከትሁ ፤ እነሆም ፥ በመካከላቸው ፡
ሌላ ፡ ትንሽ ፡ ቀንድ ፡ ወጣ ፥ በፊቱም ፡ ከቀደ
ሙት ፡ ቀንዶች ፡ ሦስት ፡ ተነቃቀሉ ፤ እነሆም ፥
በዚያ ፡ ቀንድ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ዓይኖች ፡ የነበሩ ፡
ዓይኖች ፡ በትዕቢትም ፡ የሚናገር ፡ አፍ ፡ ነበ
ሩበት ።
፱፤ ዙፋኖችም ፡ እስኪዘረጉ ፡ ድረስ ፡ አየሁ ፥
በዘመናት ፡ የሸመገለውም ፡ ተቀመጠ ፤ ልብ
ሱም ፡ እንደ ፡ በረዶ ፡ ነጭ ፥ የራሱም ፡ ጠጕር ፡
እንደ ፡ ጥሩ ፡ ጥጥ ፡ ነበረ ፤ ዙፋኑም ፡ የእሳት ፡
ነበልባል ፡ ነበረ ፥ መንኰራኵሮቹም ፡ የሚነ
፲፤ ድድ ፡ እሳት ፡ ነበሩ ። የእሳትም ፡ ፈሳሽ ፡ ከፊቱ ፡
ይፈልቅና ፡ ይወጣ ፡ ነበር ፤ ሺህ ፡ ጊዜ ፡ ሺህ ፡
ያገለግሉት ፡ ነበር ፥ እልፍ ፡ አእላፋትም ፡ በፊቱ ፡
ቆመው ፡ ነበር ፤ ፍርድም ፡ ሆነ ፥ መጻሕፍትም ፡
፲፩፤ ተገለጡ ። የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ቀንዱ ፡ ይናገ
ረው ፡ ከነበረው ፡ ከታላቁ ፡ ቃል ፡ ድምፅ ፡ የተ
ነሣ ፡ አየሁ ፤ አውሬይቱም ፡ እስክትገደል ፥
አካልዋም ፡ እስኪጠፋ ፡ ድረስ ፥ በእሳትም ፡
ለመቃጠል ፡ እስክትሰጥ ፡ ድረስ ፡ አየሁ ።
፲፪፤ ከቀሩትም ፡ አራዊት ፡ ግዛታቸው ፡ ተወሰደ ፤
የሕይወታቸው ፡ ዕድሜ ፡ ግን ፡ እስከ ፡ ዘመንና ፡
እስከ ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡ ረዘመ ።
፲፫፤ በሌሊት ፡ ራእይ ፡ አየሁ ፤ እነሆም ፥ የሰው ፡
ልጅ ፡ የሚመስል ፡ ከሰማይ ፡ ደመናት ፡ ጋር ፡
መጣ ፡ በዘመናት ፡ ወደ ፡ ሸመገለውም ፡ ደረሰ ፤
፲፬፤ ወደ ፡ ፊቱም ፡ አቀረቡት ። ወገኖችና ፡ አሕ
ዛብ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ቋንቋም ፡ የሚናገሩ ፡ ሁሉ ፡
ይገዙለት ፡ ዘንድ ፡ ግዛትና ፡ ክብር ፡ መንግሥ
ትም ፡ ተሰጠው ፤ ግዛቱም ፡ የማያልፍ ፡ የዘላ
ለም ፡ ግዛት ፡ ነው ፥ መንግሥቱም ፡ የማይጠፋ ፡
ነው ።
፲፭፤ በእኔም ፡ በዳንኤል ፡ በሥጋዬ ፡ ውስጥ ፡ መን
ፈሴ ፡ ደነገጠች ፥ የራሴም ፡ ራእይ ፡ አስቸገረኝ ።
፲፮፤ በዚያም ፡ ከቆሙት ፡ ወደ ፡ አንዱ ፡ ቀርቤ ፡ ስለ
ዚህ ፡ ሁሉ ፡ እውነቱን ፡ ጠየቅሁት ፤ እርሱም ፡
፲፯፤ ነገረኝ ፥ የነገሩንም ፡ ፍቺ ፡ አስታወቀኝ ። እን
ዚህ ፡ አራቱ ፡ ታላላቅ ፡ አራዊት ፡ ከምድር ፡
፲፰፤ የሚነሡ ፡ አራት ፡ ነገሥታት ፡ ናቸው ። ነገር ፡
ግን ፡ የልዑሉ ፡ ቅዱሳን ፡ መንግሥቱን ፡ ይወስ
ዳሉ ፥ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ዓለምም ፡ መንግሥቱን ፡
፲፱፤ ይወርሳሉ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከቀሩት ፡ ሁሉ ፡
ተለይታ ፡ እጅግ ፡ ስለምታስፈራው ፥ ጥርሶች
ዋም ፡ የብረት ፡ ጥፍሮችዋም ፡ የናስ ፡ ስለሆኑት ፥
ስለምትበላውና ፡ ስለምታደቅቀው ፡ የቀረው
ንም ፡ በእግርዋ ፡ ስለምትረግጠው ፡ ስለ ፡ አራተኛ
፳፤ ይቱ ፡ አውሬ ፥ በራስዋም ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ነበሩ ፡
ስለ ፡ አሥር ፡ ቀንዶች ፥ በኋላም ፡ ስለ ፡ ወጣው ፥
በፊቱም ፡ ሦስቱ ፡ ስለ ፡ ወደቁ ፥ ዓይኖችና ፡ ትዕ
ቢት ፡ የተናገረ ፡ አፍ ፡ ስለ ፡ ነበሩት ፥ መልኩም ፡

ከሌሎች ፡ ስለ ፡ በለጠ ፡ ስለ ፡ ሌላው ፡ ቀንድ ፡
፳፩ እውነቱን ፡ ለማወቅ ፡ ፈቀድሁ ። እነሆም ፥ ያ ፡
፳፪ ቀንድ ፡ ከቅዱሳን ፡ ጋር ፡ ሲዋጋ ፡ አየሁ ፥ በዘ
መናት ፡ የሸመገለው ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፥ ፍር
ድም ፡ ለልዑሉ ፡ ቅዱሳን ፡ እስኪሰጥ ፡ ድረስ ፥
ቅዱሳኑም ፡ መንግሥቱን ፡ የሚወስዱበት ፡
ዘመን ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ አሸነፋቸውም ።
፳፫ እንዲህም ፡ አለ ፡— አራተኛይቱ ፡ አውሬ ፡
በምድር ፡ ላይ ፡ አራተኛ ፡ መንግሥት ፡ ትሆና
ለች ፤ እርሱም ፡ ከመንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ የተ
ለየ ፡ ይሆናል ፥ ምድሪቱንም ፡ ሁሉ ፡ ይበላል ፥
፳፬ ይረግጣታል ፡ ያደቅቃትማል ። አሥሩም ፡ ቀን
ዶች ፡ ከዚያ ፡ መንግሥት ፡ የሚነሡ ፡ አሥር ፡ ነገ
ሥታት ፡ ናቸው ፤ ከእነርሱም ፡ በኋላ ፡ ሌላ ፡ ይነ
ሣል ፥ እርሱም ፡ ከፊተኞች ፡ የተለየ ፡ ይሆ
ናል ፥ ሦስቱንም ፡ ነገሥታት ፡ ያዋርዳል ።
፳፭ በልዑሉም ፡ ላይ ፡ ቃልን ፡ ይናገራል ፥ የልዑ
ልንም ፡ ቅዱሳን ፡ ይሰባብራል ፥ ዘመናትንና ፡
ሕግን ፡ ይለውጥ ፡ ዘንድ ፡ ያስባል ፤ እስከ ፡ ዘመ
ንና ፡ እስከ ፡ ዘመናት ፡ እስከ ፡ እኵሌታ ፡ ዘመ
፳፮ ንም ፡ በእጁ ፡ ይሰጣሉ ። ነገር ፡ ግን ፡ ፍርድ ፡
ይሆናል ፥ እስከ ፡ ፍጻሜም ፡ ድረስ ፡ ያፈርሱ
ትና ፡ ያጠፉት ፡ ዘንድ ፡ ግዛቱን ፡ ያስወግዱታል ።
፳፯ መንግሥትም ፡ ግዛትም ፡ ከሰማይም ፡ ሁሉ ፡
በታች ፡ ያሉ ፡ የመንግሥታት ፡ ታላቅነት ፡ ለል
ዑሉ ፡ ቅዱሳን ፡ ሕዝብ ፡ ይሰጣል ፤ መንግሥቱ ፡
የዘላለም ፡ መንግሥት ፡ ነው ፥ ግዛቶችም ፡ ሁሉ ፡
፳፰ ይገዙለታል ፡ ይታዘዙለትማል ። የነገሩም ፡
ፍጻሜ ፡ እስከዚህ ፡ ድረስ ፡ ነው ። እኔም ፡ ዳን
ኤል ፡ በአሳቤ ፡ እጅግ ፡ ተቸገርሁ ፥ ፊቴም ፡
ተለወጠብኝ ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ ነገሩን ፡ በልቤ ፡ ጠብ
ቄአለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ በመጀመሪያ ፡ ከተገለጠልኝ ፡ ራእይ ፡ በኋላ ፥
ንጉሡ ፡ ብልጣሶር ፡ በነገሠ ፡ በሦስተኛው ፡
ዓመት ፥ ለእኔ ፡ ለዳንኤል ፡ ራእይ ፡ ተገለጠ
፪ ልኝ ። በራእዩም ፡ አየሁ ፤ ባየሁም ፡ ጊዜ ፡ በኤ
ላም ፡ አውራጃ ፡ ባለው ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡ ነበርሁ ፤
በራእዩም ፡ አየሁ ፡ በኡባል ፡ ወንዝም ፡ አጠ
፫ ገብ ፡ ነበርሁ ። ዓይኔን ፡ አንሥቼ ፡ አየሁ ፤ እነ
ሆም ፥ ሁለት ፡ ቀንዶች ፡ የነበሩት ፡ አንድ ፡
አውራ ፡ በግ ፡ በወንዙ ፡ ፊት ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፥
ሁለቱም ፡ ቀንዶቹ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይሉ ፡ ነበር ፤
አንዱ ፡ ግን ፡ ከሁለተኛው ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ነበረ ፥
፬ ታላቁም ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ ወጥቶ ፡ ነበር ። አው
ራውም ፡ በግ ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ወደ ፡ ሰሜንም ፡
ወደ ፡ ደቡብም ፡ በቀንዱ ፡ ሲጐሽም ፡ አየሁ ፤
አራዊትም ፡ ሁሉ ፡ ይቋቋሙት ፡ ዘንድ ፡ አልቻ
ሉም ፥ ከእጁም ፡ የሚያድን ፡ አልነበረም ፤
እንደ ፡ ፈቃዱም ፡ አደረገ ፥ ራሱንም ፡ ታላቅ ፡
አደረገ ።
፭ እኔም ፡ ስመለከት ፥ እነሆ ፥ ከምዕራብ ፡ ወገን ፡
አንድ ፡ አውራ ፡ ፍየል ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡
ላይ ፡ ወጣ ፥ ምድርንም ፡ አልነካም ፤ ለፍየ
ሉም ፡ በዓይኖቹ ፡ መካከል ፡ አንድ ፡ ታላቅ ፡
፮ ቀንድ ፡ ነበረው ። ሁለትም ፡ ቀንድ ፡ ወዳለው ፡
በወንዝም ፡ ፊት ፡ ቆሞ ፡ ወዳየሁት ፡ አውራ ፡
በግ ፡ መጣ ፥ በኃይሉም ፡ ቍጣ ፡ ፈጥኖ ፡ ወደ ፡
፯ እርሱ ፡ ሮጠ ። ወደ ፡ አውራውም ፡ በግ ፡ ሲቀርብ ፡
አየሁት ፤ እርሱም ፡ ተመረረበት ፥ አውራው
ንም ፡ በግ ፡ መታ ፥ ሁለቱንም ፡ ቀንዶች ፡ ሰበረ ፤
አውራውም ፡ በግ ፡ ሊቋቋመው ፡ ኃይል ፡ አል
ነበረውም ፥ እርሱም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ጥሎ ፡
ረገጠው ፤ አውራውንም ፡ በግ ፡ ከእጁ ፡ ያድነው ፡
፰ ዘንድ ፡ የሚችል ፡ አልነበረም ። አውራውም ፡
ፍየል ፡ ራሱን ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ አደረገ ፤ በበረ
ታም ፡ ጊዜ ፡ ታላቁ ፡ ቀንዱ ፡ ተሰበረ ፥ ወደ ፡
አራቱም ፡ የሰማይ ፡ ነፋሳት ፡ የሚመለከቱ ፡
አራት ፡ ቀንዶች ፡ ከበታቹ ፡ ወጡ ።
፱ ከእነርሱም ፡ ከአንደኛው ፡ አንድ ፡ ታናሽ ፡
ቀንድ ፡ ወጣ ፥ ወደ ፡ ደቡብም ፡ ወደ ፡ ምሥራ
ቅም ፡ ወደ ፡ መልካሚቱም ፡ ምድር ፡ እጅግ ፡
፲ ከፍ ፡ አለ ። እስከ ፡ ሰማይም ፡ ሠራዊት ፡ ድረስ ፡
ከፍ ፡ አለ ፤ ከሠራዊትና ፡ ከከዋክብትም ፡ አያ
ሌዎችን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ጣለ ፥ ረገጣቸውም ።
፲፩ እስከ ፡ ሠራዊትም ፡ አለቃ ፡ ድረስ ፡ ራሱን ፡
ታላቅ ፡ አደረገ ፤ ከእርሱም ፡ የተነሣ ፡ የዘወ
ትሩ ፡ መሥዋዕት ፡ ተሻረ ፥ የመቅደሱም ፡
፲፪ ስፍራ ፡ ፈረሰ ። ሠራዊቱም ፡ ከኃጢአት ፡ የተ
ነሣ ፡ ከዘወትሩ ፡ መሥዋዕት ፡ ጋር ፡ ተሰጠው ፤
እርሱም ፡ እውነትን ፡ ወደ ፡ ምድሩ ፡ ጣለ ፥
፲፫ አደረገም ፡ ተከናወነም ። ከቅዱሳኑም ፡ አንዱ ፡
ሲናገር ፡ ሰማሁ ፤ ለተናገረው ፡ ለቅዱሱም ፡
ሁለተኛው ፡ ቅዱስ ፡— ስለ ፡ ዘወትሩ ፡ መሥዋ
ዕት ፥ መቅደሱና ፡ ሠራዊቱም ፡ ይረገጡ ፡ ዘንድ ፡
ስለሚሰጥና ፡ ስለሚያጠፋ ፡ ኃጢአት ፡ የሆነው ፡
፲፬ ራእይ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ይሆናል ? አለው ። እር
ሱም ፡— እስከ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡
ማታና ፡ ጥዋት ፡ ድረስ ፡ ነው ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡
መቅደሱ ፡ ይነጻል ፡ አለኝ ።
፲፭ እኔም ፡ ዳንኤል ፡ ራእዩን ፡ ባየሁ ፡ ጊዜ ፡ ማስ
ተዋሉን ፡ ፈለግሁ ፤ እነሆም ፥ የሰው ፡ ምስያ ፡
፲፮ በፊቴ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ። በኡባልም ፡ ወንዝ ፡ መካ
ከል ፡— ገብርኤል ፡ ሆይ ፥ ራእዩን ፡ ለዚህ ፡
ሰው ፡ አስታውቀው ፡ ብሎ ፡ የሚጮኸውን ፡
፲፯ የሰውን ፡ ድምፅ ፡ ሰማሁ ። እኔም ፡ ወደ ፡ ቆም
ሁበት ፡ ቀረበ ፤ በመጣም ፡ ጊዜ ፡ ፈርቼ ፡ በግ
ምባሬ ፡ ተደፋሁ ፤ እርሱም ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡
ሆይ ፥ ራእዩ ፡ ለፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
፲፰ አስተውል ፡ አለኝ ። ሲናገረኝም ፡ ደንግጬ ፡
በምድር ፡ ላይ ፡ በግምባሬ ፡ ተደፋሁ ፤ እርሱም ፡
፲፱ ዳሰሰኝ ፡ ቀጥ ፡ አድርጎም ፡ አቆመኝ ። እንዲ
ህም ፡ አለኝ ፡— እነሆ ፥ በመቅሠፍቱ ፡ በመጨ
ረሻ ፡ ዘመን ፡ የሚሆነውን ፡ አስታውቅሃለሁ ፤
ይህ ፡ ለተወሰነው ፡ ለፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ ነውና ።
፳ ባየኸው ፡ በአውራው ፡ በግ ፡ ላይ ፡ የነበሩ ፡
ሁለቱ ፡ ቀንዶች ፡ እነርሱ ፡ የሜዶንና ፡ የፋርስ ፡ ነገ

፳፩፡ ሥታት፡ናቸው። አውራውም፡ፍየል፡የግሪክ፡
ንጉሥ፡ነው፤ በዓይኖቹም፡መካከል፡ያለው፡
ታላቁ፡ቀንድ፡መጀመሪያው፡ንጉሥ፡ነው።
፳፪፡ እርሱም፡በተሰበረ፡ጊዜ፡በእርሱ፡ፋንታ፡
አራቱ፡እንደ፡ተነሡ፥እንዲሁ፡ከወገኑ፡
አራት፡መንግሥታት፡ይነሣሉ፥ነገር፡ግን፡
፳፫፡ በኃይል፡አይተካከሉትም። በመንግሥታቸ
ውም፡መጨረሻ፥ኃጢአታቸው፡በተሞላች፡
ጊዜ፥እንቈቅልሽን፡የሚያስተውል፡ፊተ፡
፳፬፡ ጨካኝ፡ንጉሥ፡ይነሣል። ኃይሉም፡ይበረ
ታል፥ነገር፡ግን፡በራሱ፡ኃይል፡አይደለም፤
በድንቅም፡ያጠፋል፥ያደርግማል፥ይከናወ
ንማል፤ኃያላንንና፡የቅዱሳንን፡ሕዝብ፡ያጠ
፳፭፡ ፋል። በመታለሉ፡ተንኰልን፡በእጁ፡ያከና
ውናል፤በልቡም፡ይታበያል፥ታምነውም፡
የሚኖሩትን፡ብዙዎችን፡ያጠፋል፤በአለቆ
ቹም፡አለቃ፡ላይ፡ይቋቋማል፤ያለ፡እጅም፡
፳፮፡ ይሰበራል። የተነገረውም፡የማታውና፡የጥ
ዋቱ፡ራእይ፡እውነተኛ፡ነው፤ነገር፡ግን፡
ከብዙ፡ዘመን፡በኋላ፡ስለሚሆን፡ራእዩን፡
፳፯፡ ዝጋ። እኔም፡ዳንኤል፡ተኛሁ፥አያሌም፡ቀን፡
ታመምሁ፤ከዚያም፡በኋላ፡ተነሥቼ፡የንጉ
ሡን፡ሥራ፡እሠራ፡ነበር፤ስለ፡ራእዩም፡
አደንቅ፡ነበር፥የሚያስተውለው፡ግን፡አል
ነበረም።

## ምዕራፍ፡፱።

፩፡ በከለዳውያን፡መንግሥት፡ላይ፡በነገሠ፥ከሜ
ዶን፡ዘር፡በነበረ፡በአሕሻዊሮስ፡ልጅ፡በዳ
፪፡ ርዮስ፡በመጀመሪያ፡ዓመት፥በነገሠ፡በመጀ
መሪያው፡ዓመት፡እኔ፡ዳንኤል፡የኢየሩሳ
ሌም፡መፍረስ፡የሚፈጸምበትን፡ሰባውን፡
ዓመት፥እግዚአብሔር፡በቃሉ፡ለነቢዩ፡ለኤ
ርምያስ፡የተናገረውን፡የዓመቱን፡ቍጥር፡
በመጽሐፍ፡አስተዋልሁ።
፫፡ ማቅ፡ለብሼ፡በአመድም፡ላይ፡ሆኜ፡ስጾም፡
እጸልይና፡እለምን፡ዘንድ፡ፊቴን፡ወደ፡ጌታ፡
፬፡ ወደ፡አምላክ፡አቀናሁ። ወደ፡አምላኬም፡
ወደ፡እግዚአብሔር፡ጸለይሁ፥ተናዘዝሁም፡
እንዲህ፡አልሁ፦ጌታ፡ሆይ፥ከሚወድዱ
ህና፡ትእዛዝህን፡ከሚፈጽሙ፡ጋር፡ቃል፡
ኪዳንንና፡ምሕረትን፡የምትጠብቅ፡ታላቅና፡
፭፡ የምታስፈራ፡አምላክ፡ሆይ፥ኃጢአትን፡ሠር
ተናል፥በድለንማል፥ክፋትንም፡አድርገ
ናል፥ዐምፀንማል፥ከትእዛዝህና፡ከፍርድ
፮፡ ህም፡ፈቀቅ፡ብለናል! በስምህም፡ለነገሥታ
ቶቻችንና፡ለአለቆቻችን፡ለአባቶቻችንም፡
ለአገሩም፡ሕዝብ፡ሁሉ፡የተናገሩትን፡ባሪያ
፯፡ ዎችህን፡ነቢያትን፡አልሰማንም። ጌታ፡ሆይ፥
ጽድቅ፡ለአንተ፡ነው፤እንደ፡ዛሬም፡ለእኛ፡
ለይሁዳ፡ሰዎችና፡በኢየሩሳሌም፡ለሚቀመጡ፡
ለእስራኤልም፡ሁሉ፡በቅርብና፡በሩቅም፡
ላሉት፡አንተን፡በበደሉበት፡በበደላቸው፡
ምክንያት፡በበተንህበት፡አገር፡ሁሉ፡የፊት፡
እፍረት፡ነው። ፰፡ ጌታ፡ሆይ፥በአንተ፡ላይ፡
ኃጢአት፡ስለ፡ሠራን፡ለእኛና፡ለነገሥታቶቻ
ችን፡ለአለቆቻችንና፡ለአባቶቻችንም፡የፊት፡
እፍረት፡ነው። ፱፡፲፡ በእርሱ፡ላይ፡ምንም፡እንኳ፡
ያመፅን፡ብንሆን፥በባሪያዎቹም፡በነቢያት፡
እጅ፡በፊታችን፡ባኖረው፡በሕጉ፡እንሄድ፡
ዘንድ፡የአምላካችንን፡የእግዚአብሔርን፡ቃል፡
ምንም፡እንኳ፡ባንሰማ፥ለጌታ፡ለአምላካ
ችን፡ምሕረትና፡ይቅርታ፡ነው። ፲፩፡ እስራኤ
ልም፡ሁሉ፡ሕግህን፡ተላልፈዋል፥ቃልህንም፡
እንዳይሰሙ፡ፈቀቅ፡ብለዋል፤በእርሱ፡ላይ፡
ኃጢአት፡ሠርተናልና፡በእግዚአብሔር፡ባሪያ፡
በሙሴ፡ሕግ፡የተጻፈው፡መሐላና፡እርግ
ማን፡ፈሰሰብን። ፲፪፡ እጅግ፡ክፉ፡ነገርንም፡
በእኛ፡ላይ፡በማምጣቱ፡በላያችንና፡በእኛ፡
ዘንድ፡በተሾሙት፡ፈራጆቻችን፡ላይ፡የተና
ገረውን፡ቃል፡አጸና፤በኢየሩሳሌምም፡ላይ፡
እንደ፡ተደረገው፡ያለ፡ነገር፡ከቶ፡ከሰማይ፡
ሁሉ፡በታች፡አልተደረገም። ፲፫፡ በሙሴም፡
ሕግ፡እንደ፡ተጻፈ፡ይህ፡ክፉ፡ነገር፡ሁሉ፡
መጣብን፤ከኃጢአታችንም፡እንመለስ፡እው
ነትህንም፡እናስብ፡ዘንድ፡ወደ፡አምላካችን፡
ወደ፡እግዚአብሔር፡ፊት፡አልለመንንም።
፲፬፡ ስለዚህም፡እግዚአብሔር፡ክፉ፡ነገሩን፡
ጠብቆ፡በእኛ፡ላይ፡አመጣ፤አምላካችን፡እግ
ዚአብሔር፡በሚሠራው፡ሥራ፡ሁሉ፡ጻድቅ፡
ነውና፥እኛም፡ቃሉን፡አልሰማንምና። ፲፭፡ አሁ
ንም፡ሕዝብህን፡ከግብጽ፡ምድር፡በበረታች፡
እጅ፡ያወጣህ፥እንደ፡ዛሬም፡ቀን፡ዝና፡ለአ
ንተ፡ያገኘህ፡ጌታ፡አምላካችን፡ሆይ፥ኃጢ
አትን፡ሠርተናል፥ክፋትንም፡አድርገናል።
፲፮፡ ጌታ፡ሆይ፥ስለ፡ኃጢአታችንና፡ስለ፡አባቶ
ቻችን፡በደል፡ኢየሩሳሌምና፡ሕዝብህ፡በዙ
ሪያችን፡ላሉት፡ሁሉ፡መሰደቢያ፡ሆነዋልና፡
እንደ፡ጽድቅህ፡ሁሉ፡ቍጣህና፡መዓትህ፡
ከከተማህ፡ከኢየሩሳሌም፡ከቅዱስ፡ተራራህ፡
እንዲመለስ፡እለምንሃለሁ። ፲፯፡ አሁንም፥አምላካ
ችን፡ሆይ፥የባሪያህን፡ጸሎትና፡ልመናውን፡
ስማ፤ጌታ፡ሆይ፥በፈረሰው፡በመቅደስህ፡
ላይ፡ስለ፡አንተ፡ስትል፡ፊትህን፡አብራ።
፲፰፡ አምላኬ፡ሆይ፥በፊትህ፡የምንለምን፡ስለ፡
ብዙ፡ምሕረትህ፡ነው፡እንጂ፡ስለ፡ጽድቃ
ችን፡አይደለምና፡ጆሮህን፡አዘንብለህ፡ስማ፤
ዓይንህን፡ገልጠህ፡ጥፋታችንና፡ስምህ፡የተ
ጠራባትን፡ከተማ፡ተመልከት። ፲፱፡ አቤቱ፥ስማ!
አቤቱ፥ይቅር፡በል፤አቤቱ፥አድምጥና፡አድ
ርግ፤አምላኬ፡ሆይ፥ስምህ፡በከተማህና፡
በሕዝብህ፡ላይ፡ተጠርቶአልና፡ስለ፡ራስህ፡
አትዘግይ።
፳፡ እኔም፡ገና፡ስናገርና፡ስጸልይ፥በኃጢአቴና፡
በሕዝቤም፡በእስራኤል፡ኃጢአት፡ስናዘዝ፥
በአምላኬም፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡ስለ፡
ተቀደሰው፡ስለ፡አምላኬ፡ተራራ፡ስለምን፥
፳፩፡ ገናም፡በጸሎት፡ስናገር፡አስቀድሜ፡በራእይ፡

አይቼው ፡ የነበረው ፡ ሰው ፡ ገብርኤል ፡ እነሆ ፡ እየበረረ ፡ መጣ ፤ በማታም ፡ መሥዋዕት ፡ ጊዜ ፡ ዳሰሰኝ ። ፳፪ አስተማረኝም ፥ ተናገረኝም ፡ እንዲ ህም ፡ አለ ፡— ዳንኤል ፡ ሆይ ፥ ጥበብንና ፡ ማስ ተዋልን ፡ እሰጥህ ፡ ዘንድ ፡ አሁን ፡ መጥቻለሁ ። ፳፫ አንተ ፡ እጅግ ፡ የተወደድህ ፡ ነህና ፡ በልመናህ ፡ መጀመሪያ ፡ ላይ ፡ ትእዛዝ ፡ ወጥቶአል ፥ እኔም ፡ እነግርህ ፡ ዘንድ ፡ መጥቻለሁ ፤ አሁንም ፡ ነገ ሩን ፡ መርምር ፥ ራእዩንም ፡ አስተውል ።

፳፬ ዓመፃን ፡ ይጨርስ ፥ ኃጢአትንም ፡ ይፈጽም ፥ በደልንም ፡ ያስተሰርይ ፥ የዘላለምን ፡ ጽድቅ ፡ ያገባ ፥ ራእይንና ፡ ትንቢትን ፡ ያትም ፥ ቅዱስ ፡ ቅዱሳኑንም ፡ ይቀባ ፡ ዘንድ ፡ በሕዝብህና ፡ በቅ ድስት ፡ ከተማህ ፡ ላይ ፡ ሰባ ፡ ሱባዔ ፡ ተቀጥሮ አል ። ፳፭ ስለዚህ ፡ እወቅ ፡ አስተውልም ፤ ኢየሩሳ ሌምን ፡ መጠገንና ፡ መሥራት ፡ ትእዛዙ ፡ ከሚ ወጣበት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አለቃው ፡ እስከ ፡ መሲሕ ፡ ድረስ ፡ ሰባት ፡ ሱባዔና ፡ስድሳ ፡ ሁለት ፡ ሱባዔ ፡ ይሆናል ፤ እርስዋም ፡ በጭንቀት ፡ ዘመን ፡ ከጎዳናና ፡ ከቅጥር ፡ ጋር ፡ ትሠራለች ። ፳፮ ከስድሳ ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ሰባትም ፡ በኋላ ፡ መሲሕ ፡ ይገደላል ፥ በእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ምንም ፡ የለም ፤ የሚመጣውም ፡ አለቃ ፡ ሕዝብ ፡ ከተማይቱንና ፡ መቅደሱን ፡ ያጠፉሉ ፤ ፍጻሜውም ፡ በጐርፍ ፡ ይሆናል ፥ እስከ ፡ መጨረሻም ፡ ድረስ ፡ ጦርነት ፡ ይሆናል ፤ ጥፋትም ፡ ተቀጥሮአል ። ፳፯ እርሱም ፡ ከብዙ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ጽኑ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ለአ ንድ ፡ ሱባዔ ፡ ያደርጋል ፤ በሱባዔውም ፡ እኩ ሌታ ፡ መሥዋዕቱንና ፡ ቍርባኑን ፡ ያስቀራል ፤ በርኩሰትም ፡ ጫፍ ፡ ላይ ፡ አጥፊው ፡ ይመጣል ፤ እስከ ፡ ተቈረጠውም ፡ ፍጻሜ ፡ ድረስ ፡ መቅሠ ፍት ፡ በአጥፊው ፡ ላይ ፡ ይፈስሳል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ በፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ በቂሮስ ፡ በሦስተኛው ፡ ዓመት ፡ ብልጣሶር ፡ ለተባለው ፡ ለዳንኤል ፡ ነገር ፡ ተገለጠለት ፤ ነገሩም ፡ እውነት ፡ ነበረ ፥ እርሱም ፡ ታላቅ ፡ ጦርነት ፡ ነው ፤ ነገሩንም ፡ አስተዋለ ፥ በራእዩም ፡ ውስጥ ፡ ማስተዋል ፡ ተሰጠው ። ፪ በዚያም ፡ ወራት ፡ እኔ ፡ ዳንኤል ፡ ሦስት ፡ ሳምንት ፡ ሙሉ ፡ ሳዝን ፡ ነበርሁ ። ፫ ማለፊያ ፡ እንጀራም ፡ አልበላሁም ፥ ሥጋና ፡ ጠጅም ፡ በአፌ ፡ አልገባም ፥ ሦስቱም ፡ ሳምንት ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ ዘይት ፡ አልተቀባሁም ። ፬ ከመጀመሪያውም ፡ ወር ፡ በሀያ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ ጤግሮስ ፡ በተባለው ፡ በታላቁ ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ ሳለሁ ፥ ፭ ዓይኔን ፡ አነሣሁ ፥ እነሆም ፥ በፍታ ፡ የለበሰውን ፡ ጥሩም ፡ የአፌዝን ፡ ወርቅ ፡ በወገቡ ፡ ላይ ፡ የታጠቀውን ፡ ሰው ፡ አየሁ ። ፮ አካሉም ፡ እንደ ፡ ቢረሌ ፡ ይመስል ፡ ነበር ፥ ፊቱም ፡ እንደ ፡ መብረቅ ፡ ምስያ ፡ ነበረ ፥ ዓይ ኖቹም ፡ እንደሚነበለበል ፡ ፋና ፥ ክንዶቹና ፡ እግሮቹም ፡ እንደ ፡ ጋለ ፡ ናስ ፥ የቃሉም ፡ ድምፅ ፡ እንደ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ድምፅ ፡ ነበረ ። ፯ እኔም ፡ ዳንኤል ፡ ብቻዬን ፡ ራእዩን ፡ አየሁ ፥ ከእኔ ፡ ጋር ፡ የነበሩ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ራእዩን ፡ አላዩም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ጽኑ ፡ መንቀጥቀጥ ፡ ወደቀባቸው ፥ ሊሸ ሸጉም ፡ ሸሹ ። ፰ እኔም ፡ ብቻዬን ፡ ቀረሁ ፡ ይህ ንም ፡ ታላቅ ፡ ራእይ ፡ አየሁ ፤ ኃይልም ፡ አልቀ ረልኝም ፥ ደም ፡ ግባቴም ፡ ወደ ፡ ማሸብሸብ ፡ ተለወጠብኝ ፥ ኃይልም ፡ አጣሁ ። ፱ የቃሉንም ፡ ድምፅ ፡ ሰማሁ ፤ የቃሉንም ፡ ድምፅ ፡ በሰማሁ ፡ ጊዜ ፡ ደንግጬ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በግምባሬ ፡ ተደፋሁ ።

፲ እነሆም ፥ አንዲት ፡ እጅ ፡ ዳሰሰችኝ ፥ በጕ ልበቴና ፡ በእጄም ፡ አቆመችኝ ። ፲፩ እርሱም ፡— እጅግ ፡ የተወደድህ ፡ ሰው ፡ ዳንኤል ፡ ሆይ ፥ እኔ ፡ ዛሬ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ተልኬአለሁና ፡ የምነ ግርህን ፡ ቃል ፡ አስተውል ፥ ቀጥ ፡ ብለህም ፡ ቁም ፡ አለኝ ። ይህንም ፡ ቃል ፡ ባለኝ ፡ ጊዜ ፡ እየተንቀጠቀጥሁ ፡ ቆምሁ ። ፲፪ እርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡— ዳንኤል ፡ ሆይ ፥ አትፍራ ፤ ልብህ ፡ ያስተውል ፡ ዘንድ ፥ ሰውነትህም ፡ በአምላክህ ፡ ፊት ፡ ይዋረድ ፡ ዘንድ ፡ ካደረግህበት ፡ ከመጀ መሪያው ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ ቃልህ ፡ ተሰምቶአል ፤ እኔም ፡ ስለ ፡ ቃልህ ፡ መጥቻለሁ ። ፲፫ የፋርስ ፡ መንግሥት ፡ አለቃ ፡ ግን ፡ ሀያ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ተቋቋመኝ ፤ እነሆም ፥ ከዋነኞቹ ፡ አለቆች ፡ አንዱ ፡ ሚካኤል ፡ ሊረዳኝ ፡ መጣ ፤ እኔም ፡ ከፋ ርስ ፡ ነገሥታት ፡ ጋር ፡ በዚያ ፡ ተውሁት ። ፲፬ ራእዩም ፡ ገና ፡ ለብዙ ፡ ዘመን ፡ ነውና ፡ በኋለ ኛው ፡ ዘመን ፡ ለሕዝብህ ፡ የሚሆነውን ፡ አስታ ውቅህ ፡ ዘንድ ፡ አሁን ፡ መጥቻለሁ ። ፲፭ ይህንም ፡ ቃል ፡ በተናገረኝ ፡ ጊዜ ፡ ፊቴን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ አቀረቀርሁ ፥ ዲዳም ፡ ሆንሁ ። ፲፮ እነሆም ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ የሚመስል ፡ ከንፈሬን ፡ ዳሰሰኝ ፤ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ አፌን ፡ ከፍቼ ፡ ተናገርሁ ፡ በፊቴም ፡ ቆሞ ፡ የነበረውን ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ ከራእዩ ፡ የተነሣ ፡ ሕመሜ ፡ መጣብኝ ፥ ኃይ ልም ፡ አጣሁ ። ፲፯ ይህ ፡ የጌታዬ ፡ ባሪያ ፡ ከዚህ ፡ ከጌታዬ ፡ ጋር ፡ ይናገር ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ይችላል ? አሁንም ፡ ኃይል ፡ አጣሁ ፥ እስትንፋስም ፡ አልቀረልኝም ፡ አልሁት ።

፲፰ ደግሞ ፡ ሰው ፡ የሚመስል ፡ ዳሰሰኝ ፥ አበረ ታኝም ። ፲፱ እርሱም ፡— እጅግ ፡ የተወደድህ ፡ ሰው ፡ ሆይ ፥ አትፍራ ፤ ሰላም ፡ ለአንተ ፡ ይሁን ፤ በርታ ፥ ጽና ፡ አለኝ ። በተናገረኝም ፡ ጊዜ ፡ በረ ታሁና ፡— አበርትተኸኛልና ፡ ጌታዬ ፡ ይናገር ፡ አልሁ ። ፳ እርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡— ወደ ፡ አንተ ፡ የመጣሁት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ታውቃለህን ? አሁንም ፡ ከፋርስ ፡ አለቃ ፡ ጋር ፡ እዋጋ ፡ ዘንድ ፡ እመለሳለሁ ፤ እኔም ፡ ስወጣ ፥ እነሆ ፤ የግሪክ ፡ አለቃ ፡ ይመጣል ። ፳፩ ነገር ፡ ግን ፡ በእ ውነት ፡ ጽሑፍ ፡ የተጻፈውን ፡ እነግርሃለሁ ፤ በዚ ህም ፡ ነገር ፡ ከአለቃችሁ ፡ ከሚካኤል ፡ በቀር ፡ ማንም ፡ የሚያጸናኝ ፡ የለም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ እኔም ፡ በሜዶናዊው ፡ በዳርዮስ ፡ መጀመሪያ ፡ ዓመት ፡ አጸናውና ፡ አበረታው ፡ ዘንድ ፡ ቆሜ ፡ ነበር ።

፪ አሁንም ፡ እውነትን ፡ አሳይሃለሁ ። እነሆ ÷ ሦስት ፡ ነገሥታት ፡ ደግሞ ፡ በፋርስ ፡ ይነሣሉ ፤ አራተኛውም ፡ ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ እጅግ ፡ ባለጠጋ ፡ ይሆናል ፤ በባለጠግነቱም ፡ በበረታ ፡ ጊዜ ፡ በግሪክ ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ ሁሉን ፡ ያስነሣል ።

፫ ኃያልም ፡ ንጉሥ ፡ ይነሣል ÷ በትልቅ ፡ አገዛዝም ፡ ይገዛል ÷ እንደ ፡ ፈቃዱም ፡ ያደርጋል ።

፬ እርሱም ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ መንግሥቱ ፡ ይሰበራል ፤ እስከ ፡ አራቱ ፡ የሰማይ ፡ ነፋሳት ፡ ይከፋፈላል ። ለዘሩ ፡ ግን ፡ አይከፋፈልም ÷ እንደ ፡ ገዛበትም ፡ አገዛዝ ፡ አይሆንም ፤ መንግሥቱ ፡ ይነቀላልና ፤ ከእነዚህም ፡ ለሌሎች ፡ ይሆናልና ።

፭ የደቡብም ፡ ንጉሥ ፡ ከአለቆቹም ፡ አንዱ ፡ ይበረታሉ ፤ እርሱም ፡ ይበረታበታል ፡ ይሠለጥንማል ፤ ግዛቱም ፡ ታላቅ ፡ ግዛት ፡ ይሆናል ።

፮ ከዘመናትም ፡ በኋላ ፡ ይጋጠማሉ ፤ የደቡብም ፡ ንጉሥ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ለማድረግ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ንጉሥ ፡ ትመጣለች ፤ የክንድዋ ፡ ኃይል ፡ ግን ፡ አይጸናም ÷ እርሱና ፡ ክንዱም ፡ አይጸናም ፤ እርስዋና ፡ እርስዋን ፡ ያመጡ ፡ የወለዳትም ፡ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ያጸናት ፡ አልፈው ፡ ይሰጣሉ ።

፯ ነገር ፡ ግን ፡ ከሥርዋ ፡ ቍጥቋጥ ፡ አንዱ ፡ በስፍራው ፡ ይነሣል ፤ ወደ ፡ ሠራዊቱም ፡ ይመጣል ÷ ወደ ፡ ሰሜንም ፡ ንጉሥ ፡ አምባ ፡ ይገባል ÷ በላያቸውም ፡ ያደርጋል ÷ ያሸንፍማል ።

፰ አማልክቶቻቸውንና ፡ ቀልጠው ፡ የተሠሩትን ፡ ምስሎቻቸውን ፡ ከብርና ፡ ከወርቅም ፡ የተሠሩትን ፡ የከበሩትን ፡ ዕቃዎች ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ይማርካል ፤ እስከ ፡ ጥቂትም ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ከሰሜን ፡ ንጉሥ ፡ ጋር ፡ ሳይዋጋ ፡ ይቀመጣል ።

፱ ይህም ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ ንጉሥ ፡ መንግሥት ፡ ይገባል ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ገዛ ፡ ምድሩ ፡ ይመለሳል ።

፲ ልጆቹም ፡ ይዋጋሉ ፤ ብዙ ፡ ሠራዊትንና ፡ ሕዝብን ፡ ይሰበስባል ፤ እርሱም ፡ ይመጣል ÷ ይጐርፍማል ÷ ያልፍማል ፤ ተመልሶም ፡ እስከ ፡ አምባው ፡ ድረስ ፡ ይዋጋል ።

፲፩ የደቡብም ፡ ንጉሥ ፡ ይቈጣል ፡ ወጥቶም ፡ ከሰሜን ፡ ንጉሥ ፡ ጋር ፡ ይዋጋል ፤ ብዙ ፡ ሕዝብንም ፡ ለሰልፍ ፡ ያቆማል ÷

፲፪ ሕዝቡም ፡ አልፎ ፡ በእጁ ፡ ይሰጣል ። ሕዝቡም ፡ በተወሰደ ፡ ጊዜ ፡ ልቡ ፡ ይታበያል ፤ እእላፋትንም ፡ ይጥላል ÷ ነገር ፡ ግን ፡ አያሸንፍም ።

፲፫ የሰሜንም ፡ ንጉሥ ፡ ይመለሳል ÷ ከቀድሞውም ፡ የበለጠ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ለሰልፍ ፡ ያቆማል ፤ በዘመናትና ፡ በዓመታትም ፡ ፍጻሜ ፡ ከታላቅ ፡ ሠራዊትና ፡ ከብዙ ፡ ሀብት ፡ ጋር ፡ ይመጣል ።

፲፬ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ በደቡብ ፡ ንጉሥ ፡ ላይ ፡ ይነሣሉ ፤ ከሕዝብህም ፡ መካከል ፡ የዓመፅ ፡ ልጆች ፡ ራእዩን ፡ ያጸኑ ፡ ዘንድ ፡ ይነሣሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ይወድቃሉ ።

፲፭ የሰሜንም ፡ ንጉሥ ፡ ይመጣል ÷ አፈርንም ፡ ይደለድላል ÷ የተመሸገችንም ፡ ከተማ ፡ ይወስዳል ፤ የደቡብም ፡ ሠራዊት ፡ የተመረጡትም ፡ ሕዝቡ ፡ አይቆሙም ፤ ለመቋቋምም ፡ ኃይል ፡ የላቸውም ።

፲፮ በእርሱም ፡ ላይ ፡ የሚመጣው ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ፈቃዱ ፡ ያደርጋል ÷ በፊቱም ፡ የሚቆም ፡ የለም ፤ በመልካሚቱም ፡ ምድር ፡ ይቆማል ÷ በእጁም ፡ ውስጥ ፡ ጥፋት ፡ ይሆናል ።

፲፯ ከመንግሥቱም ፡ ሁሉ ፡ ኃይል ፡ ጋር ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ ፊቱን ፡ ያቀናል ÷ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ አንድነትን ፡ ያደርጋል ፤ ያረክሳትም ፡ ዘንድ ፡ ሴትን ፡ ልጅ ፡ ይሰጠዋል ፤ እርስዋም ፡ አትጸናም ፡ ለእርሱም ፡ አትሆንም ።

፲፰ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ፊቱን ፡ ወደ ፡ ደሴቶች ፡ ይመልሳል ÷ ብዙዎችንም ፡ ይወስዳል ፤ አንድ ፡ አለቃ ፡ ግን ፡ ስድቡን ፡ ይሽራል ÷ ስድቡንም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ይመልሳል ።

፲፱ ፊቱንም ፡ ወደ ፡ ገዛ ፡ ምድሩ ፡ አምባዎች ፡ ይመልሳል ፤ ተሰናክሎም ፡ ይወድቃል ÷ አይገኝምም ።

፳ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ በመንግሥቱ ፡ ክብር ፡ መካከል ፡ አስገባሪውን ፡ የሚያሳልፍ ፡ በስፍራው ፡ ይነሣል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በቍጣው ፡ ሳይሆን ፡ በሰልፍም ፡ ሳይሆን ፡ በጥቂት ፡ ቀን ፡ ይሰበራል ።

፳፩ በእርሱም ፡ ስፍራ ፡ የተጠቃ ፡ ሰው ፡ ይነሣል ፡ የመንግሥቱንም ፡ ክብር ፡ አይሰጡትም ፤ በቀስታ ፡ መጥቶ ፡ መንግሥቱን ፡ በማታለል ፡ ይገዛል ።

፳፪ የሚጐርፍም ፡ ሠራዊት ፡ ከፊቱ ፡ ይወሰዳል ÷ እርሱና ፡ የቃል ፡ ኪዳኑ ፡ አለቃም ፡ ይሰበራሉ ።

፳፫ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ከተወዳጀ ፡ በኋላ ፡ በተንኰል ፡ ያደርጋል ፤ ከጥቂትም ፡ ሕዝብ ፡ ጋር ፡ ወጥቶ ፡ ይበረታል ።

፳፬ በቀስታም ፡ ከአገር ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ለመለመችው ፡ ክፍል ፡ ይገባል ፤ አባቶቹና ፡ የአባቶቹ ፡ አባቶች ፡ ያላደረጉትንም ፡ ያደርጋል ፤ ብዝበዛውንና ፡ ምርኮውንም ፡ ሀብቱንም ፡ በመካከላቸው ፡ ይበትናል ፤ በምሽጎችም ፡ ላይ ፡ እስከ ፡ ጊዜው ፡ ድረስ ፡ አሳቡን ፡ ይፈጥራል ።

፳፭ በታላቅም ፡ ሠራዊት ፡ ሆኖ ፡ ኃይሉንና ፡ ልቡን ፡ በደቡብ ፡ ንጉሥ ፡ ላይ ፡ ያስነሣል ፤ የደቡብም ፡ ንጉሥ ፡ በታላቅና ፡ በብዙ ፡ ሠራዊት ፡ ሆኖ ፡ በሰልፍ ፡ ይዋጋል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አሳብ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ይፈጥራሉና ፡ አይጸናም ።

፳፮ መብሉንም ፡ የሚበሉ ፡ ሰዎች ፡ ይሰብሩታል ፤ ሠራዊቱም ፡ ይጐርፋል ፤ ብዙዎችም ፡ ተገድለው ፡ ይወድቃሉ ።

፳፯ እነዚህም ፡ ሁለት ፡ ነገሥታት ፡ ክፋትን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ በልባቸው ፡ ያስባሉ ÷ በአንድ ፡ ገበታም ፡ ተቀምጠው ፡ ሐሰት ፡ ይናገራሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ፍጻሜው ፡ እስከ ፡ ተወሰነው ፡ ጊዜ ፡ ነውና ፡ አይከናወንላቸውም ።

፳፰ ከብዙም ፡ ሀብት ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ምድሩ ፡ ይመለሳል ÷ ልቡም ፡ በተቀደሰው ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፤ ፈቃዱንም ፡ ያደርጋል ÷ ወደ ፡ ገዛ ፡ ምድሩም ፡ ይመለሳል ።

፳፱ በተወሰነውም ፡ ጊዜ ፡ ይመለሳል ፡ ወደ ፡ ደቡብም ፡ ይመጣል ፤

ነገር ፡ ግን ፡ ኋለኛው ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ አይሆንም ። ፴ የኪቲም ፡ መርከቦች ፡ ይመጡበታልና ፡ ስለዚህ ፡ አዝኖ ፡ ይመለሳል ፥ በቅዱሱም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ላይ ፡ ይቈጣል ፥ ፈቃዱንም ፡ ያደርጋል ፤ ተመልሶም ፡ ቅዱሱን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ የተዉትን ፡ ሰዎች ፡ ይመለከታል ። ፴፩ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ሠራዊቶች ፡ ይቆማሉ ፥ መቅደሱንም ፡ ግንቡንም ፡ ያረክሳሉ ፥ የዘወትሩንም ፡ መሥዋዕት ፡ ያስቀራሉ ፥ የጥፋትንም ፡ ርኵሰት ፡ ያቆማሉ ። ፴፪ ቃል ፡ ኪዳኑን ፡ የሚበድሉትንም ፡ በማታለል ፡ ያስታል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አምላካቸውን ፡ የሚያውቁ ፡ ሕዝብ ፡ ይበረታሉ ፥ ያደርጋሉም ። ፴፫ በሕዝቡም ፡ መካከል ፡ ያሉ ፡ ጥበበኞች ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ ያስተምራሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በሰይፍና ፡ በእሳት ፡ ነበልባል ፡ በምርኮና ፡ በመበዝበዝ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ይወድቃሉ ። ፴፬ በወደቁም ፡ ጊዜ ፡ በጥቂት ፡ እርዳታ ፡ ይረዳሉ ፤ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ በግብዝነት ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ተባብረው ፡ ይሰበሰባሉ ። ፴፭ እስከ ፡ ተወሰነውም ፡ ዘመን ፡ ይሆናልና ፡ ከጥበበኞቹ ፡ አያሌዎቹ ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ ይነጥሩና ፡ ይጠሩ ፡ ይነጡም ፡ ዘንድ ፡ ይወድቃሉ ።

፴፮ ንጉሡም ፡ እንደ ፡ ፈቃዱ ፡ ያደርጋል ፤ ራሱንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ፥ በአማልክት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ራሱን ፡ ታላቅ ፡ ያደርጋል ፥ በአማልክትም ፡ አምላክ ፡ ላይ ፡ በትዕቢት ፡ ይናገራል ፤ ቍጣም ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ ይከናወንለታል ፥ የተወሰነው ፡ ይደረጋልና ። ፴፯ የአባቶቹንም ፡ አማልክት ፡ የሴቶችንም ፡ ምኞት ፡ አይመለከትም ፤ ራሱንም ፡ በሁሉ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ያደርጋልና ፡ አማልክትን ፡ ሁሉ ፡ አይመለከትም ። ፴፰ በእነዚህ ፡ ፋንታ ፡ ግን ፡ የአምባዎቹን ፡ አምላክ ፡ ያከብራል ፤ አባቶቹም ፡ ያላወቁትን ፡ አምላክ ፡ በወርቅና ፡ በብር ፡ በዕንቍና ፡ በከበረ ፡ ነገር ፡ ያከብረዋል ። ፴፱ በእንግዳም ፡ አምላክ ፡ እርዳታ ፡ በጽኑ ፡ አምባ ፡ ላይ ፡ ያደርጋል ፤ ለሚያውቁት ፡ ክብር ፡ ያበዛላቸዋል ፥ በብዙም ፡ ላይ ፡ ያስገዛቸዋል ፥ ምድርንም ፡ በዋጋ ፡ ይከፍላል ።

፵ በፍጻሜ ፡ ዘመንም ፡ የደቡብ ፡ ንጉሥ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይዋጋል ፤ የሰሜንም ፡ ንጉሥ ፡ ከሰረገሎችና ፡ ከፈረሰኞች ፡ ከብዙም ፡ መርከቦች ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ይመጣበታል ፤ ወደ ፡ አገሮችም ፡ ይገባል ፥ ይጐርፍማል ፥ ያልፍማል ። ፵፩ ወደ ፡ መልካሚቱም ፡ ምድር ፡ ይገባል ፥ ብዙ ፡ አገሮችም ፡ ይወድቃሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ኤዶምያስና ፡ ሞዓብ ፡ ከአሞንም ፡ ልጆች ፡ የበለጡት ፡ ከእጁ ፡ ይድናሉ ። ፵፪ እጁን ፡ በአገሮች ፡ ላይ ፡ ይዘረጋል ፥ የግብጽም ፡ ምድር ፡ አታመልጥም ። ፵፫ በወርቅና ፡ በብርም ፡ መዝገብ ፡ ላይ ፥ በከበረችም ፡ በግብጽ ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ይሠለጥናል ፤ የልብያና ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰዎችም ፡ ይከተሉታል ። ፵፬ ከምሥራቅና ፡ ከሰሜን ፡ ግን ፡ ወሬ ፡ ያውከዋል ፤ ብዙ ፡ ሰዎችንም ፡ ይገድል ፡ ዘንድና ፡ ፈጽሞ ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ በታላቅ ፡ ቍጣ ፡ ይወጣል ። ፵፭ ንጉሣዊ ፡ ድንኳኑንም ፡ በባሕርና ፡ በከበረው ፡ በቅዱሱ ፡ ተራራ ፡ መካከል ፡ ይተክላል ፤ ወደ ፡ ፍጻሜው ፡ ግን ፡ ይመጣል ፥ ማንም ፡ አይረዳውም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ስለ ፡ ሕዝብህ ፡ ልጆች ፡ የሚቆመው ፡ ታላቁ ፡ አለቃ ፡ ሚካኤል ፡ ይነሣል ፤ ሕዝብም ፡ ከሆነ ፡ ጀምሮ ፡ እስከዚያ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ያለ ፡ ያልሆነ ፡ የመከራ ፡ ዘመን ፡ ይሆናል ፤ በዚያም ፡ ዘመን ፡ በመጽሐፉ ፡ ተጽፎ ፡ የተገኘው ፡ ሕዝብህ ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ ይድናል ። ፪ በምድርም ፡ ትቢያ ፡ ውስጥ ፡ ከንቀላፉቱ ፡ ብዙዎች ፡ ይነቃሉ ፤ እኵሌቶቹ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ሕይወት ፥ እኵሌቶቹም ፡ ወደ ፡ እፍረትና ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ጕስቍልና ። ፫ ጥበበኞቹም ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ፀዳል ፥ ብዙ ፡ ሰዎችንም ፡ ወደ ፡ ጽድቅ ፡ የሚመልሱ ፡ እንደ ፡ ከዋክብት ፡ ለዘላለም ፡ ይደምቃሉ ። ፬ ዳንኤል ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ግን ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ ቃሉን ፡ ዝጋ ፥ መጽሐፉንም ፡ አትም ፤ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ይመረምራሉ ፥ እውቀትም ፡ ይበዛል ።

፭ እኔም ፡ ዳንኤል ፡ አየሁ ፤ እነሆም ፥ ሁለት ፡ ሌሎች ፡ ቆመው ፡ ነበር ፥ አንዱ ፡ በዚህ ፡ በወንዙ ፡ ዳር ፥ ሌላውም ፡ በዚያ ፡ በወንዙ ፡ ዳር ። ፮ አንዱም ፡ ከወንዙ ፡ ውኃ ፡ በላይ ፡ የነበረውን ፡ በፍታም ፡ የለበሰውን ፡— የዚህ ፡ ድንቅ ፡ ፍጻሜ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ? አለው ። ፯ ከወንዙም ፡ ውኃ ፡ በላይ ፡ የነበረው ፡ በፍታም ፡ የለበሰው ፡ ሰው ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ እጁን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አንሥቶ ፡— ለዘመንና ፡ ለዘመናት ፡ ለዘመንም ፡ እኵሌታ ፡ ነው ፤ የተቀደሰውም ፡ ሕዝብ ፡ ኃይል ፡ መበተን ፡ በተጨረሰ ፡ ጊዜ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ይፈጸማል ፡ ብሎ ፡ ለዘላለም ፡ ሕያው ፡ ሆኖ ፡ በሚኖረው ፡ ሲምል ፡ ሰማሁ ። ፰ ሰማሁም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አላስተዋልሁም ፤ የዚያን ፡ ጊዜም ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ የዚህ ፡ ሁሉ ፡ ፍጻሜ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አልሁ ። ፱ እርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡— ዳንኤል ፡ ሆይ ፥ ቃሉ ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ የተዘጋና ፡ የታተመ ፡ ነውና ፡ ሂድ ፤ ፲ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ሰውነታቸውን ፡ ያጠራሉ ፡ ያነጡማል ፡ ይነጥሩማል ፤ ክፉዎች ፡ ግን ፡ ክፋትን ፡ ያደርጋሉ ፤ ክፉዎችም ፡ ሁሉ ፡ አያስተውሉም ፥ ጥበበኞች ፡ ግን ፡ ያስተውላሉ ። ፲፩ የዘወትሩም ፡ መሥዋዕት ፡ ከቀረ ፡ ጀምሮ ፥ የጥፋትም ፡ ርኵሰት ፡ ከቆመ ፡ ጀምሮ ፡ ሺህ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ዘጠና ፡ ቀን ፡ ይሆናል ። ፲፪ የሚታገሥ ፥ እስከ ፡ ሺህ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ አምስት ፡ ቀንም ፡ የሚደርስ ፡ ምስጉን ፡ ነው ። ፲፫ አንተ ፡ ግን ፡ እስከ ፡ ፍጻሜው ፡ ድረስ ፡ ሂድ ፤ አንተም ፡ ታርፋለህ ፥ በቀኑም ፡ መጨረሻ ፡ በዕጣ ፡ ክፍልህ ፡ ትቆማለህ ።

# ት ን ቢ ተ ፡ ሆ ሴ ዕ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ በዖዝያንና ፡ በኢዮአታም ፡ በአካዝና ፡ በሕዝቅያስም ፡ ዘመን ፡ በእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ በዮአስ ፡ ልጅ ፡ በኢዮርብዓም ፡ ዘመን ፡ ወደ ፡ ብኤሪ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ሆሴዕ ፡ የመጣ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ።

፪፤ እግዚአብሔር ፡ መጀመሪያ ፡ በሆሴዕ ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ÷ እግዚአብሔር ፡ ሆሴዕን ፡— ምድሪቱ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ርቃ ፡ ታላቅ ፡ ግልሙትና ፡ ታደርጋለችና ፡ ሂድ ፤ ጋለሞታን ፡ ሴትና ፡ የግልሙትናን ፡ ልጆች ፡ ለአንተ ፡ ውሰድ ፡ አለው ።
፫፤ እርሱም ፡ ሄዶ ፡ የዴቤላይምን ፡ ልጅ ፡ ጎሜርን ፡ አገባ ፤ እርስዋም ፡ ፀነሰች ፡ ወንድ ፡ ልጅንም ፡
፬፤ ወለደችለት ። እግዚአብሔርም ፡— ከጥቂት ፡ ዘመን ፡ በኋላ ፡ የኢይዝራኤልን ፡ ደም ፡ በኢዩ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ እበቀላለሁና ÷ ከእስራኤልም ፡ ቤት ፡ መንግሥትን ፡ እሽራለሁና ፡ ስሙን ፡ ኢይዝራ
፭፤ ኤል ፡ ብለህ ፡ ጥራው ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ በኢይዝራኤል ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ የእስራኤልን ፡ ቀስት ፡
፮፤ እሰብራለሁ ፡ አለው ። ደግሞ ፡ ፀነሰች ፡ ሴት ፡ ልጅንም ፡ ወለደች ። እግዚአብሔርም ፡— ይቅር ፡ እላቸው ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤልን ፡ ቤት ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አልምርምና ፡ ስምዋን ፡ ሎሩሃማ ፡ ብለህ ፡ ጥራት ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የይሁዳን ፡ ቤት ፡
፯፤ እምራለሁ ፤ በአምላካቸውም ፡ በእግዚአብሔር ፡ አድናቸዋለሁ ፡ እንጂ ፡ በቀስት ፡ ወይም ፡ በሰይፍ ፡ ወይም ፡ በሰልፍ ፡ ወይም ፡ በፈረሶች ፡ ወይም ፡ በፈረሰኞች ፡ አላድናቸውም ፡ አለው ።
፰፤ ሎሩሃማም ፡ ጡት ፡ በስጣለች ፡ ጊዜ ÷ ደግሞ ፡
፱፤ ፀነሰች ፡ ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ወለደች ። እግዚአብሔርም ፡— ሕዝቤ ፡ አይደላችሁምና ÷ እኔም ፡ አምላክ ፡ አልሆናችሁምና ፡ ስሙን ፡ ሎዓሚ ፡ ብለህ ፡ ጥራው ፡ አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ቍጥር ፡ እንደማይሰፈርና ፡ እንደማይቈጠር ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ አሸዋ ፡ ይሆናል ፤ እንዲህም ፡ ይሆናል ፤ እናንተ ፡ ሕዝቤ ፡ አይደላችሁም ፡ ተብሎ ፡ በተነገረበት ፡ በዚያ ፡ ስፍራ ፡ የሕያው ፡ አምላክ ፡ ልጆች ፡ ይባላሉ ።
፪፤ የይሁዳ ፡ ልጆችና ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በአንድነት ፡ ይሰበሰባሉ ÷ ለእነርሱም ፡ አንድ ፡ አለቃ ፡ ይሾማሉ ÷ ከምድሪቱም ፡ ይወጣሉ ፤ የኢይዝራኤል ፡ ቀን ፡ ታላቅ ፡ ይሆናልና ።
፫፤ ወንድሞቻችሁን ፡— ዓሚ ÷ እኅቶቻችሁንም ፡— ሩሃማ ፡ በሉአቸው ።

፬፤ እናታችሁ ፡ ሚስቴ ፡ አይደለችምና ÷ እኔም ፡

ባልዋ፡አይደለሁምና፡ተምዋገቱ፤ከእናታችሁ፡
ጋር ፡ ተምዋገቱ ። ግልሙትናዋን ፡ ከፊትዋ ÷
ምንዝርናዋንም ፡ ከጡቶችዋ ፡ መካከል ፡ ታስ
፫፤ ወግድ ፤ ዕራቁትዋን ፡ እንዳልገፍፋት ÷ እንደ፡
ተወለደችበትም፡ቀን፡እንዳላደርጋት ÷ እንደ፡
ምድረ ፡ በዳና ፡ እንደ ፡ ደረቅ ፡ ምድር ፡ እንዳላ
፬፤ ደርጋት ÷ በጥማትም ፡ እንዳልገድላት ፤ የግል
ሙትናዋ ፡ ልጆች ፡ ናቸውና ፡ ልጆችዋን፡አል
፭፤ ምርም ። እናታቸው ፡ አመንዝራለች ፤ የፀነሰ
ቻቸውም ፡— እንጀራዬንና ፡ ውኃዬን ÷ ጥጤ
ንና ፡ የተልባ ፡ እግሬን÷ዘይቴንና ፡ መጠጤን፡
ከሚሰጡኝ ፡ ከውሽሞቼ ፡ በኋላ ፡ እሄዳለሁ ፡
፮፤ ብላ ፡ አስነወረቻቸው ። ስለዚህ÷ እነሆ÷ መንገ
ድሽን ፡ በእሾህ ፡ እዘጋለሁ ÷ መንገድዋንም ፡
፯፤ እንዳታገኝ ፡ ቅጥርን ፡ እቀጥርባታለሁ ። ውሽ
ሞችዋንም ፡ ትከተላለች ÷ ነገር ፡ ግን ፡ አት
ደርስባቸውም ፤ ትፈልጋቸውማለች ÷ ነገር ፡
ግን ፡ አታገኛቸውም ፤ እርስዋም ፡— ከዛሬ ፡
ይልቅ፡የዚያን፡ጊዜ፡ይሻለኝ፡ነበርና፡ተመ
ልሼ፡ወደ ፡ ቀደመው ፡ ባሌ ፡ እሄዳለሁ ፡ ትላ
ለች ።

፰፤ እርስዋም፡ እህልንና ፡ ወይንን፡ጠጅ፡ዘይ
ትንም፡የሰጠኋት ÷ ለበአልም፡የተሠራውን፡
ብርና፡ወርቅ፡ያበዛሁላት፡እኔ፡እንደ፡ሆንሁ፡
፱፤ አላወቀችም ። ስለዚህ ፡ እህሌን ፡ በጊዜዋ ÷
ወይን፡ጠጄንም፡በወረትዋ፡እወስዳለሁ÷ዕራ
ቁትነትዋንም ፡ እንዳትሸፍን ፡ ጥጤንና ፡ የተ
፲፤ ልባ፡እግሬን፡እገፍፋታለሁ።አሁንም፡ውሽሞ
ችዋ፡እያዩ፡ነውርዋን፡እገልጣለሁ፤ከእጄም፡
፲፩፤ ማንም ፡ አያድናትም ። ደስታዋንም ፡ ሁሉ ÷
በዓላቶችዋንም÷መባቻዎችዋንም÷ሰንበቶች
ዋንም÷የተቀደሱትንም፡ጉባኤዎችን፡ሁሉ፡
፲፪፤ አስቀራለሁ ። እርስዋም ፡— ውሽሞቼ ፡ የሰ
ጡኝ፡ዋጋዬ፡ይህ፡ነው፡ ያለችውን ፡ ወይን
ዋንና፡በለስዋን፡አጠፋለሁ ፤ ዱርም፡አደርገ
ዋለሁ÷የምድረ፡በዳም፡አራዊት፡ይበሉታል።
፲፫፤ እኔን፡ረስታ ፡ ውሽሞችዋን ፡ እየተከተለች ÷
በጉትቾችዋና ፡ በጌጥዋም ፡ እያጌጠች ፡ ለበአ
ሊም፡ያጠነችበትን፡ወራት፡እበቀልባታለሁ÷
ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፲፬፤ ስለዚህ ÷ እነሆ ÷ አባብላታለሁ ÷ ወደ ፡
ምድረ ፡ በዳም ፡ አመጣታለሁ ÷ ለልብዋም ፡
፲፭፤ እናገራለሁ ። ከዚያም ፡ የወይን ፡ ቦታዋን ÷
የተስፋ፡በርም፡እንዲሆንላት፡የአኮርን፡ሸለቆ፡
እሰጣታለሁ፤በዚያም፡ከግብጽ፡ምድር፡እንደ፡
ወጣችበት ፡ ቀን፡ እንደ ፡ ሕፃንነትዋ ፡ ወራት ፡
፲፮፤ ትዘምራለች ። በዚያ ፡ ቀን፡ባሌ፡ብለሽ፡ትጠሪ
ኛለሽ፡እንጂ ፡ ዳግመኛ ፡ በአሌ ፡ ብለሽ ፡ አትጠ
፲፯፤ ሪኝም ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ የበአሊምን ፡
ስም ፡ ከአፍዋ ፡ አስወግዳቸዋለሁና ÷ በስማቸ
፲፰፤ ውም ፡ እንግዲህ ፡ አይታሰቡምና ። በዚያም ፡
ቀን ፡ ከምድር ፡ አራዊትና ፡ ከሰማይ ፡ ወፎች ፡
ከመሬትም ፡ ተንቀሳቃሾች ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን፡
አደርግላቸዋለሁ ፤ ቀስትንና ፡ ሰይፍን ፡ ሰልፍ
ንም ፡ ከምድሩ ፡ እሰብራለሁ ÷ ተከልለውም ፡
፲፱፤ እንዲኖሩ፡አስተኛቸዋለሁ ። ለዘላለምም፡ለእኔ፡
እንድትሆኚ፡አጭሻለሁ ፤ በጽድቅና፡በፍርድ፡
፳፤ በምሕረትና፡በርኅራኄ ፡ አጭሻለሁ ። ለእኔም፡
እንድትሆኚ፡በመታመን፡አጭሻለሁ፤እንቺም፡
እግዚአብሔርን ፡ ታውቂአለሽ ።

፳፩፤ በዚያንም ፡ ቀን ፡ እመልሳለሁ ÷ ይላል ፡ እግ
ዚአብሔር ፤ ለሰማይ ፡ እመልሳለሁ ÷ ሰማይም፡
፳፪፤ ለምድር ፡ ይመልሳል ፤ ምድርም ፡ ለእህልና ፡
ለወይን ፡ ጠጅ ፡ ለዘይትም ፡ ትመልሳለች ፤ እነ
፳፫፤ ርሱም ፡ ለኢይዝራኤል ፡ ይመልሳሉ ። በምድ
ርም ፡ ላይ ፡ ለእኔ ፡ እዘራታለሁ ፤ ምሕረትም ፡
የሌላትን ፡ እምራለሁ ÷ ሕዝቤም ፡ ያልሆነ
ውን ፡— አንተ ፡ ሕዝቤ ፡ ነህ ፡ እለዋለሁ ፤ እር
ሱም ፡— አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነህ ፡ ይለኛል ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፤ እግዚአብሔርም ፡— የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ወደ፡ሌሎች፡አማልክት፡ቢመለሱና፡የዘቢብ፡
ጥፍጥፍን ፡ ቢወድዱ ፡ እንኳ ÷ እግዚአብሔር፡
እንደሚወድዳቸው ፡ አንተም ፡ ውሽማዋን ፡
የምትወድደውን ፡ አመንዝራይትን ፡ ሴት ፡
፪፤ ውደድ ፡ አለኝ ። እኔም ፡ በአሥራ ፡ አምስት ፡
ብርና ፡ በአንድ ፡ ቆሮስ ፡ መስፈሪያ ፡ ተኩል ፡
፫፤ ገብስ ፡ ገዛኋት ። ከእኔ ፡ ጋር ፡ ብዙ ፡ ወራት ፡
ተቀመጪ ÷ አታመንዝሪም ÷ ለሌላ ፡ ሰውም፡
አትሁኚ ፤ እኔም ፡ እንዲሁ ፡ እሆንልሻለሁ ፡ አል
፬፤ ኋት ። የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ያለ ፡ ንጉሥና ፡
ያለ፡አለቃ÷ያለ፡መሥዋዕትና፡ያለ፡ዓምድ÷
ያለ ፡ ኤፉድና ፡ ያለ ፡ ተራፊም ፡ ብዙ ፡ ወራት ፡
፭፤ ይቀመጣሉና ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ተመልሰው ፡ አምላካቸውን ፡ እግዚአ
ብሔርንና፡ንጉሣቸውን፡ዳዊትን፡ይፈልጋሉ፤
በኋለኛውም ፡ ዘመን ፡ ፈርተው ፡ ወደ ፡ እግዚ
አብሔርና ፡ ወደ ፡ በረከቱ ፡ ይመጣሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩፤ እናንተ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ÷ እው
ነትና ፡ ምሕረት ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ማወቅ ፡
በምድር ፡ ስለሌለ ፡ እግዚአብሔር ፡ በምድሩ ፡
ላይ ፡ ከሚኖሩ ፡ ጋር ፡ ክርክር ፡ አለውና ፡ የእግ
፪፤ ዚአብሔርን፡ ቃል ፡ስሙ ። እርግማንና ፡ ሐሰት ፡
ግዳይና ፡ ስርቆት ፡ ምንዝርናም ፡ ወጥተዋል ፤
፫፤ ደምም ፡ ወደ ፡ ደም ፡ ደርሶአል ። ስለዚህ ፡ ምድ
ሪቱ ፡ ታለቅሳለች ÷ በእርስዋም ፡ የሚቀመጡ ፡
ሁሉ ፡ ከምድር ፡ አራዊትና ፡ ከሰማይ ፡ ወፎች ፡
ጋር ፡ ይደክማሉ ፤ የባሕሩም ፡ ዓሦች ፡ ያልቃሉ ።
፬፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሕዝብህ ፡ ከካህን ፡ ጋር ፡ እንደሚከ
ራከሩ ፡ ናቸውና ፡ ማንም ፡ አይከራከር ÷ ማንም ፡
፭፤ አይዝለፍ ። በቀንም ፡ ትሰናከላለህ ÷ ነቢዩም ፡
ከአንተ ፡ ጋር ፡ በሌሊት ፡ ይሰናከላል ፤ እናትህ
ንም ፡ አጠፋታለሁ ።

፮፤ ሕዝቤ ፡ እውቀት ፡ ከማጣቱ ፡ የተነሣ ፡ ጠፍ
ቶአል ፤ አንተም ፡ እውቀትን ፡ ጠልተሃልና ፡

እኔ ፡ ካህን ፡ እንዳትሆነኝ ፡ እጠላሃለሁ ፤ የአምላክህንም ፡ ሕግ ፡ ረስተሃልና ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ ልጆችህን ፡ እረሳለሁ ። ፯ እንደ ፡ ብዛታቸው ፡ መጠን ፡ ኀጢአት ፡ ሠሩብኝ ፤ እኔም ፡ ክብራቸውን ፡ ወደ ፡ ነውር ፡ እለውጣለሁ ። ፰ የሕዝቤም ፡ ኀጢአት ፡ መብል ፡ ሆኖላቸዋል ፥ ልባቸውንም ፡ ወደ ፡ በደላቸው ፡ አድርገዋል ። ፱ እንደ ፡ ሕዝቡም ፡ እንዲሁ ፡ ካህኑ ፡ ይሆናል ፤ በመንገዳቸውም ፡ እበቀላቸዋለሁ ፥ ሥራቸውንም ፡ እመልስባቸዋለሁ ። ፲ እግዚአብሔርንም ፡ መጠበቅ ፡ ትተዋልና ፡ ሲበሉ ፡ አይጠግቡም ፥ ሲያመነዝሩም ፡ አይበዙም ።

፲፩ ግልሙትናና ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ስካርም ፡ አእምሮን ፡ ያጠፋል ። ፲፪ የግልሙትና ፡ መንፈስ ፡ ሕዝቤን ፡ አስቶአቸዋልና ፥ እነርሱም ፡ ከአምላካቸው ፡ ርቀው ፡ አመንዝረዋልና ፡ በትራቸውን ፡ ይጠይቃሉ ፥ ዘንጋቸውም ፡ ይመልስላቸዋል ። ፲፫ በተራሮችም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይሠዋሉ ፤ ጥላውም ፡ መልካም ፡ ነውና ፡ ከኮምበልና ፡ ከልብን ፡ ከአሆማም ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ በኮረብቶች ፡ ላይ ፡ ያጥናሉ ፤ ስለዚህ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችሁ ፡ ይገለሙታሉ ፥ ሙሽሮቻችሁም ፡ ያመነዝራሉ ። ፲፬ ወንዶችም ፡ ደግሞ ፡ ከጋለሞቶች ፡ ጋር ፡ ይጫወታሉና ፥ ከጋለሞቶችም ፡ ጋር ፡ ይሠዋሉና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችሁ ፡ በገለሞቱ ፡ ጊዜ ፥ ሙሽሮቻችሁም ፡ በመነዘሩ ፡ ጊዜ ፡ አልቀጣቸውም ፤ የማያስተውልም ፡ ሕዝብ ፡ ይገለበጣል ።

፲፭ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ብታመነዝር ፡ ይሁዳ ፡ አይበድል ፤ እናንተም ፡ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ አትግቡ ፥ ወደ ፡ ቤትአዌንም ፡ አትውጡ ፥ ወይም ፦ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ! ብላችሁ ፡ አትማሉ ። ፲፮ እስራኤል ፡ እንደ ፡ እልከኛ ፡ ጊደር ፡ እንቢ ፡ ብሎአል ፤ እግዚአብሔርስ ፡ በሰፊው ፡ በታ ፡ እንደ ፡ ጠቦት ፡ ያሰማራዋልን ? ፲፯ ኤፍሬም ፡ ከጣዖታት ፡ ጋር ፡ ተጋጠመ ፤ ተወው ። ፲፰ ስካርን ፡ ፈጽመዋል ፥ ግልሙትናንም ፡ አብዝተዋል ፤ ፲፱ አለቆችዋም ፡ ነውርን ፡ እጅግ ፡ ወደዱ ። ነፋስ ፡ በክንፍዋ ፡ አስሮአታል ፤ ከመሥዋዕታቸውም ፡ የተነሣ ፡ ያፍራሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ካህናት ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ ስሙ ፤ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ አድምጡ ፤ የንጉሥ ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ ልብ ፡ አድርጉ ፤ በምጽጳ ፡ ላይ ፡ ወጥመድ ፥ በታቦርም ፡ ላይ ፡ የተዘረጋ ፡ እሽክላ ፡ ሆናችኋልና ፡ ፪ ፍርድ ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ነው ። ዓመፀኞችም ፡ እርድ ፡ አብዝተዋል ፤ እኔ ፡ ግን ፡ እነዚያን ፡ ፫ ሁሉ ፡ እዘልፋለሁ ። ኤፍሬምን ፡ አውቀዋለሁ ፥ እስራኤልም ፡ ከእኔ ፡ አልተሰወረም ፤ ኤፍሬም ፡ ሆይ ፥ ዛሬ ፡ አመንዝረሃል ፥ እስራኤልም ፡ ረክሶአል ። ፬ ወደ ፡ አምላካቸው ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ ሥራቸውን ፡ አላቀኑም ፤ የግልሙትና ፡ መንፈስ ፡ በውስጣቸው ፡ አለና ፤ እግዚአብሔርንም ፡ ፭ አላወቁምና ። የእስራኤልም ፡ ትዕቢት ፡ በፊቱ ፡ ይመሰክራል ፤ ስለዚህ ፡ እስራኤልና ፡ ኤፍሬም ፡ በኃጢአታቸው ፡ ይሰናከላሉ ፤ ይሁዳም ፡ ደግሞ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ይሰናከላል ። ፮ እግዚአብሔርንም ፡ ለመሻት ፡ በጎቻቸውንና ፡ ላሞቻቸውን ፡ ነድተው ፡ ይሄዳሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ ከእነርሱ ፡ ተመልሶአልና ፡ አያገኙትም ። ፯ ዲቃሎችን ፡ ልጆች ፡ ወልደዋልና ፡ እግዚአብሔርን ፡ ወንጅለዋል ፤ አሁንም ፡ አንድ ፡ ወር ፡ እነርሱንና ፡ ርስታቸውን ፡ ይበላቸዋል ።

፰ በጊብዓ ፡ መለከትን ፥ በራማ ፡ እንቢልታን ፡ ንፉና ፦ ብንያም ፡ ሆይ ፥ ከአንተ ፡ በኋላ ፡ እያላችሁ ፡ በቤትአዌን ፡ ላይ ፡ እሪ ፡ በሉ ። ፱ ኤፍሬም ፡ በዘለፋ ፡ ቀን ፡ የፈረሰ ፡ ይሆናል ፤ በእስራኤል ፡ ነገዶች ፡ ዘንድ ፡ በእርግጥ ፡ የሚሆነውን ፡ ነገር ፡ ገልጫለሁ ። ፲ የይሁዳ ፡ አለቆች ፡ ድምበርን ፡ እንደሚነቅሉ ፡ ሆነዋል ፤ እኔም ፡ መዓቴን ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ አፈስስባቸዋለሁ ። ፲፩ ኤፍሬም ፡ ከትእዛዝ ፡ በኋላ ፡ መሄድን ፡ ወድዶአልና ፡ የተገፋና ፡ በፍርድ ፡ የተጐዳ ፡ ሆኖአል ። ፲፪ እኔም ፡ ለኤፍሬም ፡ እንደ ፡ ብል ፥ ለይሁዳም ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ነቀዝ ፡ ሆኛለሁ ። ፲፫ ኤፍሬምም ፡ ደዌውን ፥ ይሁዳም ፡ ቍስሉን ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ኤፍሬም ፡ ወደ ፡ አሦር ፡ ሄደ ፡ ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ወደ ፡ ኢያሪም ፡ መልእክተኛን ፡ ላከ ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ ይፈውሳችሁ ፡ ዘንድ ፥ ከቍስላችሁም ፡ ያድናችሁ ፡ ዘንድ ፡ አልቻለም ። ፲፬ እኔም ፡ ለኤፍሬም ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፥ ለይሁዳም ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ደቦል ፡ እሆናለሁና ፤ እኔም ፡ ነጥቄ ፡ እሄዳለሁ ፡ እወስድማለሁ ፥ የሚያድንም ፡ አይገኝም ። ፲፭ በደላቸውንም ፡ እስኪያውቁ ፡ ድረስ ፥ ፊቴንም ፡ እስኪሹ ፡ ድረስ ፡ ሄጄ ፡ ወደ ፡ ስፍራዬ ፡ እመለሳለሁ ፤ በመከራቸው ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ አድርገው ፡ ፊቴን ፡ ይፈልጋሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ኑ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንመለስ ፤ እርሱ ፡ ሰብሮናልና ፥ እርሱም ፡ ይፈውሰናል ፤ እርሱ ፡ ፪ መትቶናል ፥ እርሱም ፡ ይጠግነናል ። ከሁለት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ያድነናል ፤ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ያስነሣናል ፥ በፊቱም ፡ በሕይወት ፡ እንኖራለን ። ፫ እንወቅ ፤ እናውቀውም ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንከተል ፤ እንደ ፡ ወገግታም ፡ ተዘጋጅቶ ፡ እናገኘዋለን ፤ እንደ ፡ ዝናብም ፡ ምድርንም ፡ እንደሚያጠጣ ፡ እንደ ፡ መጨረሻ ፡ ዝናብ ፡ ይመጣል ።

፬ ምሕረታችሁ ፡ እንደ ፡ ማለዳ ፡ ደመና ፥ በማለዳም ፡ እንደሚያልፍ ፡ ጠል ፡ ነውና ፡ ኤፍሬም ፡ ሆይ ፥ ምን ፡ ላድርግልህ ? ይሁዳ ፡ ሆይ ፥ ምን ፡ ላድርግልህ ? ፭ ስለዚህ ፡ በነቢያት ፡ እጅ ፡ ቈረጥኋቸው ፥ በአፌም ፡ ቃል ፡ ገደልኋቸው ፤ ፍርዴም ፡ እንደ ፡ ብርሃን ፡ ይወጣል ። ፮ ከመሥዋዕት ፡ ይልቅ ፡ ምሕረትን ፥ ከሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ ይልቅ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ማወቅ ፡ እወድዳለሁና ። ፯ እነርሱ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ አዳም ፡

ቃል ፡ ኪዳንን ፡ ተላልፈዋል ፤ በዚያም ፡ ላይ ፡
፰፤ ወንጅለውኛል ። ገለዓድ ፡ ኃጢአትን ፡ የሚ
ሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ከተማ ፣ በደምም ፡ የተቀባ ፡
፱፤ ነው ። ለሰውም ፡ እንደሚያደቡ ፡ ወንበዴዎች ፣
እንዲሁ ፡ የካህናት ፡ ወገኖች ፡ በሴኬም ፡ መን
ገድ ፡ ላይ ፡ ይገድላሉ ፤ ሴሰኝነትንም ፡ ያደርጋሉ ።
፲፤ በእስራኤል ፡ ቤት ፡ የሚያስፈራን ፡ ነገር ፡ አይ
ቻለሁ ፤ በዚያ ፡ በኤፍሬም ፡ ውስጥ ፡ ግልሙ
ትና ፡ ተገኘ ፣ እስራኤልም ፡ ረከሰአል ።
፲፩፤ ይሁዳ ፡ ሆይ ፣ የሕዝቤን ፡ ምርኮ ፡ በምመልስ
በት ፡ ጊዜ ፡ ለአንተ ፡ ደግሞ ፡ መከር ፡ ተወስኖ
ልሃል ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩፤ በሐሰት ፡ አድርገዋልና ፣ ሌባም ፡ ገብቶአ
ልና ፣ በውጭም ፡ ወንበዴዎች ፡ ቀምተዋልና ፡
እስራኤልን ፡ እፈውስ ፡ ዘንድ ፡ በወደድሁ ፡
ጊዜ ፡ የኤፍሬም ፡ ኃጢአትና ፡ የሰማርያ ፡ ክፋት ፡
፪፤ ተገለጠ ። እኔም ፡ ክፋታቸውን ፡ ሁሉ ፡ እን
ዳሰብሁ ፡ በልባቸው ፡ አያስቡም ፤ አሁንም ፡
ሥራቸው ፡ ከብባቸዋለች ፣ በፊቴም ፡ አለች ።
፫፤ ንጉሡን ፡ በክፋታቸው ፣ አለቆቹንም ፡ በሐሰ
፬፤ ታቸው ፡ ደስ ፡ አሰኝተዋል ። ሁሉም ፡ አመን
ዝራዎች ፡ ናቸው ፤ ጋጋሪ ፡ እንደሚያነድድበት ፡
እንደ ፡ ምድጃ ፡ ናቸው ፤ ሁሉ ፡ እስኪቦካ ፡
ድረስ ፡ እሳትን ፡ መቈስቈስና ፡ እርሾን ፡ መለ
፭፤ ወስ ፡ ይቆያል ። በንጉሣችን ፡ ቀን ፡ አለቆች ፡
ከወይን ፡ ጠጅ ፡ ሙቀት ፡ የተነሣ ፡ ታመሙ ፤
እርሱም ፡ ከዋዘኞች ፡ ጋር ፡ እጁን ፡ ዘረጋ ።
፮፤ እያደቡ ፡ ልባቸውን ፡ እንደ ፡ ምድጃ ፡ አዘጋጅ
ተዋል ፤ አበዛቸውም ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ አንቀ
ላፋ ፤ በጠባም ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ነበልባል ፡
፯፤ ይነድዳል ። ሁሉም ፡ እንደ ፡ ምድጃ ፡ ግለዋል ፣
ፈራጆቻቸውንም ፡ በሉ ፤ ነገሥታቶቻቸውም ፡
ሁሉ ፡ ወደቁ ፤ ከእነርሱም ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ የሚ
ጮኽ ፡ የለም ።
፰፤ ኤፍሬም ፡ ከአሕዛብ ፡ ጋር ፡ ተደባለቀ ፤ ኤፍ
፱፤ ሬም ፡ እንዳልተገላበጠ ፡ ቂጣ ፡ ነው ። እንግ
ዶች ፡ ጕልበቱን ፡ በሉት ፣ እርሱም ፡ አላወ
ቀም ፤ ሽበትም ፡ ወጣበት ፣ እርሱም ፡ አላወ
፲፤ ቀም ። የእስራኤልም ፡ ትዕቢት ፡ በፊቱ ፡ መሰ
ከረ ፤ ወደ ፡ አምላካቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ግን ፡ አልተመለሱም ፣ በዚህም ፡ ሁሉ ፡ አል
፲፩፤ ፈለጉትም ። ኤፍሬምም ፡ አእምሮ ፡ እንደሌ
ላት ፡ እንደ ፡ ሰነፍ ፡ ርግብ ፡ ነው ፤ ግብጽን ፡
፲፪፤ ጠሩ ፣ ወደ ፡ አሦርም ፡ ሄዱ ። ሲሄዱ ፡ አሽክላ
ዬን ፡ እዘረጋባቸዋለሁ ፤ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ወፎች ፡
አወርዳቸዋለሁ ፤ መከራቸውን ፡ ሲሰሙ ፡ እገ
፲፫፤ ሥጻቸዋለሁ ። ከእኔ ፡ ፈቀቅ ፡ ብለዋልና ፡
ወዮላቸው ፤ በእኔም ፡ ላይ ፡ ዐምፀዋልና ፡ ጥፋት ፡
ይምጣባቸው ፤ እኔ ፡ ልታደጋቸው ፡ ወደድሁ ፣
፲፬፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ በሐሰት ፡ ተናገሩብኝ ። በመኝ
ታቸው ፡ ላይ ፡ ሆነው ፡ ያለቅሱ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡
በልባቸው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አልጮኹም ፤ ስለ ፡
እህልና ፡ ስለ ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡ ይሰበሰቡ ፡ ነበር ፤
፲፭፤ በእኔም ፡ ላይ ፡ ዐመፁ ። እኔም ፡ ክንዳቸውን ፡
አስተማርሁና ፡ አጸናሁ ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ ክፉ ፡
፲፮፤ ነገርን ፡ መከሩብኝ ። ወደ ፡ ከንቱ ፡ ነገር ፡ ተመ
ለሱ ፤ እንደ ፡ ተንኰለኛ ፡ ቀስት ፡ ሆኑ ፤ አለ
ቆቻቸው ፡ ከምላሳቸው ፡ ቍጣ ፡ የተነሣ ፡
በሰይፍ ፡ ይወድቃሉ ፤ ይህ ፡ በግብጽ ፡ ምድር ፡
ውስጥ ፡ መሳለቂያ ፡ ይሆንባቸዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩፤ መለከትን ፡ ወደ ፡ አፍህ ፡ አቅርብ ፤ ቃል ፡ ኪዳ
ኔን ፡ ተላልፈዋልና ፣ በሕጌም ፡ ላይ ፡ ዐምፀዋ
ልና ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ንስር ፡
፪፤ ይመጣል ። እነርሱም ፡— አምላክ ፡ ሆይ ፣ እኛ ፡
እስራኤል ፡ አወቅንህ ፡ ብለው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይጮ
፫፤ ኻሉ ። እስራኤል ፡ ደግነትን ፡ ጥሎአል ፤ ጠላ
፬፤ ትም ፡ ያሳድዱታል ። ለራሳቸው ፡ ነገሥታትን ፡
አነገሡ ፣ ከእኔም ፡ ዘንድ ፡ አይደለም ፤ አለቆች
ንም ፡ አደረጉ ፣ እኔም ፡ አላወቅሁም ፤ ለጥፋታ
ቸውም ፡ ከብራቸውና ፡ ከወርቃቸው ፡ ጣዖታ
፭፤ ትን ፡ ለራሳቸው ፡ አደረጉ ። ሰማርያ ፡ ሆይ ፣
እምቦሳህን ፤ ጥሎአል ፤ ቍጣዬ ፡ በላያቸው ፡ ነድ
ዶአል ፤ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ንጹሕ ፡ ሊሆኑ ፡
፮፤ አይችሉም ? ይህ ፡ ደግሞ ፡ ከእስራኤል ፡ ዘንድ ፡
ነው ፤ ሠራተኛ ፡ ሠራው ፣ እርሱም ፡ አምላክ ፡
አይደለም ፤ የሰማርያም ፡ እምቦሳ ፡ ይቈራረጣል ።
፯፤ ነፋስን ፡ ዘርተዋል ፣ ዐውሎ ፡ ነፋስንም ፡ ያጭ
ዳሉ ፤ አገዳ ፡ የለውም ፣ ከፍሬውም ፡ ዱቄት ፡
አይገኝም ፤ ቢገኝም ፡ እንግዶች ፡ ይበሉታል ።
፰፤ እስራኤል ፡ ተውጦአል ፣ በአሕዛብም ፡ መካ
፱፤ ከል ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡ ረከሰ ፡ ዕቃ ፡ ሆኖአል ። ለብ
ቻውም ፡ እንደሚቀመጥ ፡ እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
አህያ ፡ ወደ ፡ አሦር ፡ ወጥተዋል ፤ ኤፍሬምም ፡
፲፤ ወዳጆቹን ፡ በእጅ ፡ መንሻ ፡ ገዛ ። ነገር ፡ ግን ፡
ለአሕዛብ ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ቢሰጡ ፡ እኔ ፡ አሁን ፡
እሰበስባቸዋለሁ ፤ ከንጉሥና ፡ ከአለቆችም ፡
ሸክም ፡ የተነሣ ፡ ይደክማሉ ።
፲፩፤ ኤፍሬም ፡ ኃጢአትን ፡ ለመሥራት ፡ መሠ
ዊያ ፡ አብዝቶአልና ፡ መሠዊያ ፡ ለኃጢአት ፡
፲፪፤ ይሆንለታል ። የሕጌን ፡ ብዛት ፡ጽፌለታለሁ ፤
እነርሱ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ እንግዳ ፡ ነገር ፡ ቈጥረው
፲፫፤ ታል ። መሥዋዕቴን ፡ ያቀርባሉ ፣ ሥጋንም ፡
ያርዳሉ ፣ ይበላሉም ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ አይ
ቀበላቸውም ፤ በደላቸውንም ፡ ያስባል ፣ ኃጢ
አታቸውንም ፡ ይቀጣል ፤ እነርሱም ፡ ወደ ፡
፲፬፤ ግብጽ ፡ ይመለሳሉ ። እስራኤል ፡ ፈጣሪውን ፡
ረስቶአል ፣ መስገጃዎችንም ፡ ሠርቶአል ፤ ይሁ
ዳም ፡ የተመሸጉትን ፡ ከተሞች ፡ አብዝቶአል ፤
እኔ ፡ ግን ፡ በከተሞች ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ እሰድዳ
ለሁ ፣ አዳራሾችንም ፡ ትበላለች ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ እስራኤል ፡ ሆይ ÷ ከአምላክህ ፡ ተለይተህ ፡ አመንዝረሃልና ፡ እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ደስ ፡ አይበ ልህ ÷ ሐሴትንም ፡ አታድርግ ፤ በእህሉ ፡ አው ድማ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የግልሙትናን ፡ ዋጋ ፡ ወድ ደሃል ። ፪ አውድማውና ፡ መጥመቂያው ፡ አይመ ግባቸውም ÷ ጉሽ ፡ ጠጅም ፡ ይጐድልባታል ። ፫ በእግዚአብሔር ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ አይቀመጡም ፤ ኤፍሬምም ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ይመለሳል ÷ በአሦ ርም ፡ ርኩስን ፡ ነገር ፡ ይበላሉ ። ፬ ለእግዚአብሔ ርም ፡ የወይን ፡ ጠጅን ፡ ቍርባን ፡ አያፈስሱም ÷ መሥዋዕታቸውም ፡ ደስ ፡ አያሰኘውም ፤ የኀዘ ንም ፡ እንጀራ ፡ ይሆንላቸዋል ÷ የሚበላውም ፡ ሁሉ ፡ ይረክሳል ፤ እንጀራቸውም ፡ ለሰውነታ ቸው ፡ ይሆናል ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አይገባም ። ፭ በዓመት ፡ በዓል ፡ ቀንና ፡ በእግዚአብሔር ፡ በዓል ፡ ቀን ፡ ምን ፡ ታደርጋ ላችሁ ? ፮ እነሆ ÷ ከጥፋት ፡ ሸሽተው ፡ ሄዱ ÷ ግብጽም ፡ ትሰበስባቸዋለች ÷ ሜምፎስም ፡ ትቀ ብራቸዋለች ፤ ሳማም ፡ የብራቸውን ፡ ጌጥ ፡ ይወ ርሳል ÷ እሾህም ፡ በድንኳኖቻቸው ፡ ውስጥ ፡ ይበቅላል ። ፯ የበቀል ፡ ወራት ፡ መጥቶአል ÷ የፍዳም ፡ ወራት ፡ ደርሶአል ÷ እስራኤልም ፡ ያውቃል ፤ ከኃጢአትህና ፡ ከጠላትነትህ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ነቢዩ ፡ ሰንፎአል ÷ መንፈስም ፡ ያለ በት ፡ ሰው ፡ አብዶአል ። ፰ ኤፍሬም ፡ ከአምላኬ ፡ ጋር ፡ ተመልካች ፡ ነበረ ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ነቢዩ ፡ በመንገዱ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የወፍ ፡ ወጥመድ ፡ ሆነ ÷ በአምላኩም ፡ ቤት ፡ ጠላትነት ፡ አለ ። ፱ በጊብዓ ፡ ዘመን ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ እጅግ ፡ ረከሱ ፤ እርሱም ፡ በደላቸውን ፡ ያስባል ÷ ኃጢአታቸ ውንም ፡ ይበቀላል ።

፲ እስራኤልን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንዳለ ፡ ወይን ፡ ሆኖ ፡ አገኘሁት ፤ አባቶቻችሁንም ፡ ከመጀመ ሪያዋ ፡ ዓመት ፡ እንደ ፡ በለስ ፡ በኵራት ፡ ሆነው ፡ አየኋቸው ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ብዔልፌጎር ፡ መጡ ÷ ለነውርም ፡ ተለዩ ÷ እንደ ፡ ወደዱ ትም ፡ ርኩስ ፡ ሆኑ ። ፲፩ የኤፍሬምም ፡ ክብር ፡ እንደ ፡ ወፍ ፡ በርሮ ፡ ይጠፋል ፤ መውለድና ፡ ፲፪ መፅነስ ፡ ማርገዝም ፡ አይሆንላቸውም ። ልጆ ቻቸውንም ፡ ቢያሳድጉ ፡ ሰው ፡ እንዳይቀርላ ቸው ፡ ልጅ ፡ አልባ ፡ አደርጋቸዋለሁ ፤ ከእነር ፲፫ ሱም ፡ በራቅሁ ፡ ጊዜ ፡ ወዮላቸው ! እኔ ፡ እን ዳየሁ ፡ የኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ ለምርኮ ፡ ተሰጥተ ዋል ፤ ኤፍሬምም ፡ ልጆቹን ፡ ወደ ፡ ገዳዮች ፡ ፲፬ ያወጣል ። አቤቱ ÷ ስጣቸው ፤ ምን ፡ ትሰጣቸ ዋለህ ? የሚጨነግፍን ፡ ማኅፀን ፡ የደረቀው ፲፭ ንም ፡ ጡት ፡ ስጣቸው ። ክፋታቸው ፡ ሁሉ ፡ በጌልገላ ፡ አለ ፤ በዚያ ፡ ጠልቻቸዋለሁ ፤ ስለ ፡ ሥራት ፡ ክፋት ፡ ከቤቴ ፡ አሳድዳቸዋለሁ ፤ ከእ ንግዲህ ፡ ወዲያ ፡ አልወድዳቸውም ፤ አለቆቻ ፲፮ ቸው ፡ ሁሉ ፡ ዓመፀኞች ፡ ናቸው ። ኤፍሬም ፡ ተመታ ÷ ሥሩም ፡ ደረቀ ÷ ፍሬም ፡ አያፈራም ፤ ደግሞም ፡ ቢወልዱ ፡ የማኅፀናቸውን ፡ ፍሬ ፡ እገድላለሁ ። ፲፯ አልሰሙትምና ፡ አምላኬ ፡ ይጥ ላቸዋል ፤ በአሕዛብም ፡ መከከል ፡ ተቅበዝባ ዦች ፡ ይሆናሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ እስራኤል ፡ ፍሬው ፡ የበዛለት ፡ የለመለመ ፡ ወይን ፡ ነው ፤ እንደ ፡ ፍሬው ፡ ብዛት ፡ መሠዊ ያውን ፡ አብዝቶአል ፤ እንደ ፡ ምድሩም ፡ ማማር ፡ መጠን ፡ ሐውልቶችን ፡ እያሳመሩ ፡ ሠርተዋል ። ፪ ልባቸው ፡ ተከፈለ ፤ አሁንም ፡ በደላቸውን ፡ ይሸ ከማሉ ፤ እርሱ ፡ መሠዊያቸውን ፡ ያፈርሳል ÷ ሐውልቶቻቸውን ፡ ያጠፋል ። ፫ አሁንም ፡— ንጉሥ ፡ የለንም ÷ እግዚአብሔርን ፡ አልፈራን ምና ፤ ንጉሥስ ፡ ምን ፡ ያደርግልናል ? ይላሉ ። ፬ የማይረባውን ፡ ቃል ፡ ይናገራሉ ፤ ቃል ፡ ኪዳን ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ በሐሰት ፡ ይምላሉ ፤ ስለ ዚህ ፡ መርዛም ፡ ሣር ፡ በእርሻ ፡ ትልም ፡ ላይ ፡ እንደሚበቅል ፡ መቅሠፍት ፡ ይበቅልባቸዋል ። ፭ የሰማርያ ፡ ሰዎች ፡ ስለ ፡ ቤትአዌን ፡ እምቦሳ ፡ ይፈራሉ ፤ ክብሩም ፡ ከእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ወጥቶአ ልና ፡ ሕዝቡ ፡ ያለቅሱለታል ÷ የጣዖቱ ፡ ካህና ትም ፡ በኀዘን ፡ ይንተበተባሉ ። ፮ ለንጉሡ ፡ ለኢ ያሬም ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ አሦር ፡ ይማረካል ፤ ኤፍሬምን ፡ እፍረት ፡ ይይ ዘዋል ÷ እስራኤልም ፡ በምክሩ ፡ ያፍራል ። ፯ ሰማርያ ፡ ከንጉሥዋ ፡ ጋር ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡ እን ዳለ ፡ አረፋ ፡ ጠፍታለች ። ፰ የእስራኤል ፡ ኃጢ አት ፡ የሆኑት ፡ የአዌን ፡ የኮረብታው ፡ መስገጃ ዎች ፡ ይፈርሳሉ ፤ እሾህና ፡ አሜከላ ፡ በመሠዊ ያዎቻቸው ፡ ላይ ፡ ይበቅላል ፤ ተራሮችንም ፡— ክደኑን ÷ ኮረብቶችንም ፡— ውደቁብን ፡ ይሉ አቸዋል ።

፱ እስራኤል ፡ ሆይ ÷ ከጊብዓ ፡ ዘመን ፡ ጀም ረህ ፡ ኃጢአትን ፡ ሠርተሃል ፤ በዚያ ፡ ጸንተዋል ፤ በጊብዓ ፡ ላይ ፡ ሰልፍ ፡ አይደርስባቸውምን ? ፲ በፈቀድሁም ፡ ጊዜ ፡ እገሥጻቸዋለሁ ፤ ስለ ፡ ሁለ ቱም ፡ ኃጢአታቸው ፡ በታሰሩ ፡ ጊዜ ፡ አሕዛብ ፡ ይሰበሰቡባቸዋል ። ፲፩ ኤፍሬም ፡ ማበራየት ፡ እንደ ፡ ለመደች ፡ ጊደር ፡ ነው ÷ እኔ ፡ ግን ፡ በአንገቱ ፡ ውበት ፡ እጫንበታለሁ ፤ በኤፍሬም ፡ ላይ ፡ እጠምድበታለሁ ÷ ይሁዳም ፡ ያርሳል ÷ ያዕቆብም ፡ አፈሩን ፡ ያለሰልሳል ።

፲፪ እግዚአብሔር ፡ መጥቶ ፡ ጽድቅን ፡ እስኪያዘ ንብላችሁ ፡ ድረስ ፡ እርሱን ፡ የምትሹበት ፡ ዘመን ፡ ነውና ፡ ለእናንተ ፡ በጽድቅ ፡ ዝሩ ÷ እንደ ፡ ምሕረቱም ፡ መጠን ፡ እጨዱ ÷ ጥጋታ ችሁንም ፡ እረሱ ። ፲፫ ክፋትን ፡ አርሳችኋል ÷ ኃጢአትንም ፡ አጭዳችኋል ÷ የሐሰትንም ፡ ፍሬ ፡ በልታችኋል ፤ በኃያላንህ ፡ ብዛት ÷ በመ ንገድህም ፡ ላይ ፡ ታምነሃልና ። ፲፬ በሕዝብህም ፡ መከከል ፡ ሽብር ፡ ይነሣል ፤ እናትም ፡ ከልጆ ችዋ ፡ ጋር ፡ በተፈጠፈጠች ፡ ጊዜ ፡ ሰልማን ፡ ቤትአርብኤልን ፡ በሰልፍ ፡ ቀን ፡ እንዳፈረሰ ÷

፲፭ አምባዎችህ ፡ ሁሉ ፡ ይፈርሳሉ ። ከኃጢአታች
ሁም ፡ ክፋት ፡ የተነሣ ፡ ቤቴል ፡ እንዲሁ ፡ ያደ
ርግባችኋል ፤ በነጋ ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡
ፈጽሞ ፡ ይጠፋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ እስራኤል ፡ ሕፃን ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፡ ወደድ
፪ ሁት ፥ ልጄንም ፡ ከግብጽ ፡ ጠራሁት ። አብዝቼ ፡
ብጠራቸው ፡ አጥብቀው ፡ ከፊቴ ፡ ራቁ ፤ ለበአ
ሊምም ፡ ይሠዉ ፡ ነበር ፥ ለተቀረጹ ፡ ምስሎ
፫ ችም ፡ ያጥኑ ፡ ነበር ። እኔም ፡ ኤፍሬምን ፡ ክን
ዱን ፡ ይዤ ፡ በእግሩ ፡ እንዲሄድ ፡ መራሁት ፤
እኔም ፡ እፈውሳቸው ፡ እንደ ፡ ነበርሁ ፡ አላወ
፬ ቁም ። በሰው ፡ ገመድ ፡ በፍቅርም ፡ እስራት ፡
ሳብኋቸው ፤ ለእነርሱም ፡ ቀምበርን ፡ ከጫንቃ
ቸው ፡ ላይ ፡ እንደሚያነሣ ፡ ሆንሁ ፥ ድርቆሽም ፡
ጣልሁላቸው ።

፭ ወደ ፡ እኔ ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ አልወደዱምና ፡
ወደ ፡ ግብጽ ፡ ምድር ፡ ይመለሳሉ ፥ አሦርም ፡
፮ ንጉሣቸው ፡ ይሆናል ። ከመከሩትም ፡ ምክር ፡
የተነሣ ፡ ሰይፍ ፡ በከተሞቻቸው ፡ ላይ ፡ ይወድ
፯ ቃል ፥ ከበርቴዎችንም ፡ ያጠፋል ። ሕዝቤም ፡
ከእኔ ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ ወደዱ ፤ ወደ ፡ ላይም ፡
ቢጠሩአቸው ፡ ማንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋቸው ፡
ዘንድ ፡ አይችልም ።

፰ ኤፍሬም ፡ ሆይ ፥ እንዴት ፡ እጥልሃለሁ ?
እስራኤል ፡ ሆይ ፥ እንዴትስ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጥ
ሃለሁ ? እንዴትስ ፡ እንደ ፡ አዳማ ፡ እጥልሃለሁ ?
እንዴትስ ፡ እንደ ፡ ሲባዮ ፡ አደርግሃለሁ ? ልቤ ፡
በውስጤ ፡ ተናወጠለች ፥ ምሕረቴም ፡ ተነሣ
፱ ሥታለች ። እኔ ፡ አምላክ ፡ ነኝ ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡
አይደለሁምና ፥ በመካከልህም ፡ ቅዱሱ ፡ ነኝና ፡
የቍጣዬን ፡ መቅሠፍት ፡ አላደርግም ፥ ኤፍሬ
ምንም ፡ አጠፋ ፡ ዘንድ ፡ አልመለስም ፤ በመ
፲ ዓትም ፡ አልመጣም ። እግዚአብሔርን ፡ ይከ
ተላሉ ፥ እርሱም ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ያገሣል ፤
በገሣም ፡ ጊዜ ፡ ልጆች ፡ እየተንቀጠቀጡ ፡
፲፩ ከምዕራብ ፡ ይመጣሉ ። እንደ ፡ ወፍም ፡ ከግ
ብጽ ፥ እንደ ፡ ርግብም ፡ ከአሦር ፡ ምድር ፡ እየ
ተንቀጠቀጡ ፡ ይመጣሉ ፤ በቤታቸውም ፡ አኖ
ራቸዋለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ ኤፍሬም ፡ በሐሰት ፥ የእስራኤልም ፡ ቤት ፡
በተንኰል ፡ ከበበኝ ፤ ይሁዳም ፡ ከታመነው ፡
ቅዱሱ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ አይጸናም ።
፪ ኤፍሬም ፡ ነፋስን ፡ ይበላል ፥ የምሥራቅንም ፡
ነፋስ ፡ ይከተላል ፤ ሁልጊዜም ፡ ሐሰትንና ፡ ተን
ኰልን ፡ ያበዛል ፤ ከአሦር ፡ ጋር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
ያደርጋሉ ፥ ወደ ፡ ግብጽም ፡ ዘይት ፡ ይወስዳሉ ።
፫ እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፡ ከይሁዳ ፡ ጋር ፡ ክር
ክር ፡ አለው ፥ ያዕቆብንም ፡ እንደ ፡ መንገዱ ፡
ይቀጣል ፤ እንደ ፡ ሥራውም ፡ ይመልስለታል ።
፬ በማኅፀን ፡ ውስጥ ፡ ወንድሙን ፡ በተረከዙ ፡
ያዘው ፥ በጕልማስነቱም ፡ ጊዜ ፡ ከአምላክ ፡
፭ ጋር ፡ ታገለ ፤ ከመልአኩም ፡ ጋር ፡ ታግሎ ፡
አሸነፈ ፤ አልቅሶም ፡ ለመነው ። በቤቴልም ፡
አገኘው ፥ በዚያም ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ተነጋገረ ።
፮ እርሱም ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡
ነው ፤ የመታሰቢያው ፡ ስም ፡ እግዚአብሔር ፡
፯ ነው ። ስለዚህ ፡ ወደ ፡ አምላክህ ፡ ተመለስ ፤
ምሕረትንና ፡ ፍርድን ፡ ጠብቅ ፥ ዘወትርም ፡
በአምላክህ ፡ ታመን ።

፰ ከነዓን ፡ ወገን ፡ ነው ፤ በእጁ ፡ የተንኰል ፡
፱ ሚዛን ፡ አለ ፥ ሽንገላንም ፡ ይወድዳል ። ኤፍሬ
ምም ፦ ባለ ፡ ጠጋ ፡ ሆኜአለሁ ፥ ሀብትንም ፡
አግኝቻለሁ ፥ በድካሜም ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአት ፡
፲ የሚሆን ፡ በደል ፡ አይገኝብኝም ፡ አለ ። እኔም ፡
ከግብጽ ፡ ጀምሬ ፡ አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡
ነኝ ፤ እንደ ፡ ዓመት ፡ በዓል ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ገና ፡
፲፩ በድንኳን ፡ እንድትኖር ፡ አደርግሃለሁ ። ለነቢያ
ትም ፡ ተናግሬአለሁ ፥ ራእይንም ፡ አብዝቻ
ለሁ ፤ በነቢያትም ፡ እጅ ፡ ምሳሌዎችን ፡ አውጥ
፲፪ ቻለሁ ። ኃጢአት ፡ በገለዓድ ፡ አለ ፤ ፈጽመው ፡
ከንቱ ፡ ናቸው ፤ ወይፈኖች ፡ በጌልገላ ፡ ይሠ
ዋሉ ፥ መሠዊያዎቻቸውም ፡ በእርሻ ፡ ትልም ፡
፲፫ ላይ ፡ የድንጋይ ፡ ክምር ፡ ይሆናሉ ። ያዕቆብ ፡
ወደ ፡ ሶርያ ፡ አገር ፡ ሸሸ ፥ እስራኤልም ፡ ስለ ፡
ሚስት ፡ አገለገለ ፥ ስለ ፡ ሚስትም ፡ ጠባቂ ፡
፲፬ ነበረ ። እግዚአብሔርም ፡ በነቢይ ፡ እጅ ፡ እስራ
ኤልን ፡ ከግብጽ ፡ አወጣ ፥ በነቢይም ፡ እጅ ፡
፲፭ ጠበቀው ። ኤፍሬም ፡ አስመርሮ ፡ አስቈጣው ፤
ስለዚህ ፡ ደሙ ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ ነው ፤ ጌታውም ፡
ስድቡን ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ይመልሳል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ ኤፍሬም ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ፡ ፍርሃት ፡ ነበረ ፥
በእስራኤልም ፡ ዘንድ ፡ ታበየ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በአ
፪ ልን ፡ በማምለክ ፡ በበደለ ፡ ጊዜ ፡ ሞተ ። አሁ
ንም ፡ ኃጢአትን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ጨመሩ ፤
በብራቸውም ፡ ለራሳቸው ፡ ቀልጦ ፡ የተሠራ ፡
ምስልን ፥ እንደ ፡ ጥበባቸውም ፡ ጣዖታትን ፡
ሠርተዋል ፤ ሁሉም ፡ የሠራተኛ ፡ ሥራ ፡
ናቸው ። ስለ ፡ እነርሱም ፦ የሚሠዉ ፡ ሰዎች ፡
፫ እምቦሳውን ፡ ይሳሙ ፡ ይላሉ ። ስለዚህም ፡
እንደ ፡ ማለዳ ፡ ደመና ፥ በጥዋትም ፡ እንደሚያ
ልፍ ፡ ጠል ፥ በዐውሎ ፡ ነፋስም ፡ ከአውድማ ፡
እንደሚበተን ፡ እብቅ ፥ ከመስኮትም ፡ እንደ
ሚወጣ ፡ ጢስ ፡ ይሆናሉ ።
፬ እኔ ፡ ግን ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ጀምሬ ፡ አምላ
ክህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ፤ ከእኔም ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡
አምላክ ፡ አታውቅም ፥ ከእኔም ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡
፭ መድኃኒት ፡ የለም ። በምድረ ፡ በዳ ፥ እጅግ ፡
፮ በደረቀ ፡ ምድር ፡ አውቄህ ፡ ነበር ። ከተሰማሩ ፡
በኋላ ፡ ጠገቡ ፥ በጠገቡም ፡ ጊዜ ፡ ልባቸው ፡
፯ ታበየ ፤ ስለዚህ ፡ ረሱኝ ። ስለዚህም ፡ እኔ ፡
እንደ ፡ አንበሳ ፡ ሆንሁባቸው ፥ እንደ ፡ ነብርም ፡
፰ በመንገድ ፡ አጠገብ ፡ አደባበቻቸዋለሁ ፤ ልጅዋ ፡

እንደ፡ ተነጠቀባት፡ ድብ፡ እገጥማቸዋለሁ ÷ የልባቸውንም፡ ስብ፡ እቀድዳለሁ ፤ በዚያም፡ እንደ፡ አንበሳ፡ እበላቸዋለሁ ÷ የምድረ፡ በዳም፡ አውሬ፡ ይነጣጠቃቸዋል ።

፱ እስራኤል፡ ሆይ ÷ በእኔ፡ በረዳትህ፡ ላይ፡ ፲ በመነሣትህ፡ ጥፋትህ፡ ነው ። በየከተማህ፡ ሁሉ፡ ያድንህ፡ ዘንድ፡ ንጉሥህ፡ ወዴት፡ አለ? ስለ፡ እነርሱም፡— ንጉሥንና፡ አለቆችን፡ ስጠኝ፡ ብለህ፡ የተናገርኸው፡ መሳፍንቶችህ፡ ወዴት፡ ፲፩ አሉ ? በቍጣዬ፡ ንጉሥን፡ ሰጠሁህ ÷ በመዓ ፲፪ ቴም፡ ሻርሁት ። የኤፍሬም፡ በደል፡ ታስሮ ፲፫ አል ÷ ኃጢአቱም፡ ተከማችቶአል ። ምጥ፡ እንደ፡ ያዛት፡ ሴት፡ ጭንቅ፡ ይመጣበታል ፤ በሚወለድበት፡ ጊዜ፡ በማኅፀን፡ አፍ፡ ቀጥ፡ ብሎ፡ አይወጣምና፡ አእምሮ፡ የሌለው፡ ልጅ፡ ፲፬ ነው ። ከሲኦል፡ እጅ፡ እታደጋቸዋለሁ ÷ ከሞ ትም፡ እቤዣቸዋለሁ ፤ ሞት፡ ሆይ ÷ ቸነፈርህ፡ ወዴት፡ አለ ? ሲኦል፡ ሆይ ÷ ማጥፋትህ፡ ወዴት፡ አለ ? ርኅራኄ፡ ከዓይኔ፡ ተሰወረች ።

፲፭ በወንድሞቹ፡ መካከል፡ ፍሬያማ፡ ቢሆን፡ የምሥራቅ፡ ነፋስ፡ ይመጣል ÷ የእግዚአብሔር፡ ነፋስ፡ ከምድረ፡ በዳ፡ ይመጣል ፤ ምንጩንም፡ ያደርቃል ÷ ፈሳሹንም፡ ያጠፋል ÷ የተከበሩ፡ ዕቃዎች፡ ሁሉ፡ ያሉበትን፡ መዝገብ፡ ይበዘብ ፲፮ ዛል ። ሰማርያ፡ በአምላክዋ፡ ላይ፡ ዐምፃለ ችና፡ በደልዋን፡ ትሸከማለች ፤ በሰይፍ፡ ይወ ድቃሉ ÷ ሕፃናቶቻቸውም፡ ይፈጠፈጣሉ ÷ እር ጉዞቻቸውም፡ ይቀደዳሉ ።

## ምዕራፍ፡ ፲፬ ።

፩ እስራኤል፡ ሆይ ÷ በኃጢአትህ፡ ወድቀሃ ልና፡ ወደ፡ አምላክህ፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ ተመለስ ። ፪ ከእናንተ፡ ጋር፡ ቃልን፡ ውሰዱ ÷ ወደ፡ እግዚአብሔርም፡ ተመልሳችሁ፡— ኃጢ አትን፡ ሁሉ፡ አስወግድ ÷ በቸርነትም፡ ተቀበ ለን ÷ በወይፈንም፡ ፋንታ፡ የከንፈራችንን፡ ፍሬ፡ እንሰጣለን ። ፫ አሦር፡ አያድነንም ፤ በፈ ረስ፡ ላይ፡ አንቀመጥም ፤ ድሀ፡ አደጉም፡ በአ ንተ፡ ዘንድ፡ ምሕረትን፡ ያገኛልና፡ ከእንግ ዲህ፡ ወዲህ፡ ለእጆቻችን፡ ሥራ፡— አምላኮቻ ችን፡ ናችሁ፡ አንላቸውም፡ በሉት ።

፬ ቍጣዬ፡ ከእርሱ፡ ዘንድ፡ ተመልሶአልና፡ ዓመፃቸውን፡ እፈውሳለሁ ÷ በገዛ፡ ፈቃዴ፡ እወ ድዳቸዋለሁ ። ፭ ለእስራኤልም፡ እንደ፡ ጠል፡ እሆ ነዋለሁ ፤ እንደ፡ አበባም፡ ያብባል ÷ እንደ፡ ሊባ ኖስም፡ ሥሩን፡ ይሰድዳል ። ፮ ቅርንጫፎቹም፡ ይዘረጋሉ ÷ ውበቱም፡ እንደ፡ ወይራ ÷ ሽታ ውም፡ እንደ፡ ሊባኖስ፡ ይሆናል ። ፯ ከጥላውም፡ በታች፡ የሚቀመጡ፡ ይመለሳሉ ፤ ከእህሉም፡ የተነሣ፡ ይጠግባሉ ፤ እንደ፡ ወይንም፡ አረግ፡ ያብባሉ ፤ መታሰቢያውም፡ እንደ፡ ሊባኖስ፡ ወይን፡ ጠጅ፡ ይሆናል ። ፰ ከእንግዲህ፡ ወዲያ፡ ጣዖት፡ ለኤፍሬም፡ ምንድር፡ ነው ? እኔ፡ ሰም ቼዋለሁ ÷ ወደ፡ እርሱም፡ እመለከታለሁ ፤ እኔ፡ እንደ፡ ለመለመ፡ ጥድ፡ ነኝ ፤ ፍሬህ፡ በእኔ፡ ዘንድ፡ ይገኛል ።

፱ ይህን፡ ነገር፡ የሚያስተውል፡ ጠቢብ ÷ የሚ ያውቃትም፡ አስተዋይ፡ ማን፡ ነው ? የእግዚ አብሔር፡ መንገድ፡ ቅን፡ ነው ÷ ጻድቃንም፡ ይሄዱበታል ፤ ተላላፊዎች፡ ግን፡ ይወድቁበ ታል ።

# ትንቢተ፡ አሞጽ ።

## ምዕራፍ፡ ፩ ።

፩ በቴቁሔ፡ ከላም፡ ጠባቂዎች፡ መካከል፡ የነ በረ፡ አሞጽ፡ በይሁዳ፡ ንጉሥ፡ በዖዝያን፡ ዘመን ÷ በእስራኤልም፡ ንጉሥ፡ በዮአስ፡ ልጅ፡ በኢዮርብዓም፡ ዘመን ÷ የምድር፡ መናወጥ፡ ከሆነበቱ፡ ከሁለት፡ ዓመት፡ በፊት፡ ስለ፡ እስ ራኤል፡ ያየው፡ ቃል፡ ይህ፡ ነው ።

፪ እንዲህም፡ አለ፡— እግዚአብሔር፡ በጽዮን፡ ሆኖ፡ ድምፁን፡ ከፍ፡ አድርጎ፡ ይጮኻል ÷ በኢ የሩሳሌምም፡ ሆኖ፡ ቃሉን፡ ይሰጣል ፤ የእረኞ ችም፡ ማሰማርያዎች፡ ያለቅሳሉ ÷ የቀርሜሎ ስም፡ ራስ፡ ይደርቃል ።

፫ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡— ገለዓድን፡ በብረት፡ መንኰራኵር፡ አሂዶአልና፡ ስለ፡ ሦስት፡ ወይም፡ ስለ፡ አራት፡ የደማስቆ፡ ኃጢ አት፡ መቅሠፍቴን፡ ከማድረግ፡ አልመለስም ። ፬ በአዛሄል፡ ቤት፡ እሳትን፡ እሰድዳለሁ ÷ የወ ልደ፡ አዴርንም፡ አዳራሾች፡ ትበላለች ። ፭ የደ ማስቆንም፡ መወርወሪያ፡ እሰብራለሁ ÷ ተቀማ ጮችንም፡ ከአዌን፡ ሸለቆ፡ አጠፋለሁ ÷ በትር፡ የያዘውንም፡ ከዔደን፡ ቤት፡ አጠፋለሁ ፤ የሶ ርያም፡ ሕዝብ፡ ወደ፡ ቂር፡ ይማረካል ÷ ይላል፡ እግዚአብሔር ።

፮ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡— ለኤዶም ያስ፡ አሳልፈው፡ ይሰጡአቸው፡ ዘንድ፡ ምር ኮኞችን፡ ሁሉ፡ ማርከዋልና፡ ስለ፡ ሦስት፡ ወይም፡ ስለ፡ አራት፡ የጋዛ፡ ኃጢአት፡ መቅሠ ፍቴን፡ ከማድረግ፡ አልመለስም ። ፯ በጋዛ፡ ቅጥር፡ ላይ፡ እሳትን፡ እሰድዳለሁ ÷ አዳራሾችዋንም፡ ትበላለች ። ፰ ተቀማጮችን፡ ከአዛጦን፡ አጠፋ ለሁ ÷ በትር፡ የያዘውንም፡ ከአስቀሎና፡ አጠ ፋለሁ ፤ እጄንም፡ በአቃሮን፡ ላይ፡ እመልሳ ለሁ ÷ ከፍልስጥኤማውያንም፡ የቀሩት፡ ይጠ

ፋሉ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፱ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ምርኮኞችን ፡ ሁሉ ፡ ለኤዶምያስ ፡ አሳልፈው ፡ ሰጥተዋልና ፥ የወንድሞችንም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አላሰቡምና ፡ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የጢሮስ ፡ ኃጢአት ፡ መቅሠፍቴን ፡ ከማድረግ ፡ አል

፲ መለስም ። በጢሮስ ፡ ቅጥር ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ እሰድዳለሁ ፥ አዳራሾችዋንም ፡ ትበላለች ።

፲፩ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ወንድሙን ፡ በሰይፍ ፡ አሳድዶታልና ፥ ርኅራኄንም ፡ ሁሉ ፡ ጥሎአልና ፥ ቍጣውም ፡ ሁልጊዜ ፡ ቀድዶአልና ፥ መዓቱንም ፡ ለዘላለም ፡ ጠብቆአልና ፡ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የኤዶምያስ ፡ ኃጢአት ፡ መቅሠፍቴን ፡ ከማድረግ ፡ አልመለ

፲፪ ስም ። በቴማን ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ እሰድዳለሁ ፥ የባሶራንም ፡ አዳራሾች ፡ ትበላለች ።

፲፫ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ዳርቻቸውን ፡ ያሰፉ ፡ ዘንድ ፡ የገለዓድን ፡ እርጕዞች ፡ ቀድደዋልና ፡ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የአሞን ፡ ልጆች ፡ ኃጢአት ፡ መቅሠፍቴን ፡ ከማ

፲፬ ድረግ ፡ አልመለስም ። በረባት ፡ ቅጥር ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ አነድዳለሁ ፤ በሰልፍም ፡ ቀን ፡ በጩኸት ፡ በወውሎ ፡ ነፋስም ፡ ቀን ፡ በሁከት ፡ አዳ

፲፭ ራሾችዋን ፡ ትበላለች ፤ ንጉሣቸውም ፡ ከአለቆቹ ፡ ጋር ፡ በአንድነት ፡ ይማረካል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ የኤዶምያስን ፡ ንጉሥ ፡ አጥንት ፡ አመድ ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡ አቃጥሎታልና ፡ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የሞዓብ ፡ ኃጢአት ፡ መቅሠፍቴን ፡

፪ ከማድረግ ፡ አልመለስም ። በሞዓብ ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ እሰድዳለሁ ፥ የቂርዮትንም ፡ አዳራሾች ፡ ትበላለች ፤ ሞዓብም ፡ በውካታና ፡ በጩ

፫ ኸት ፡ በመለከትም ፡ ድምፅ ፡ ይሞታል ፤ ፈራጁንም ፡ ከመካከልዋ ፡ አጠፋለሁ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ አለቆችዋን ፡ ሁሉ ፡ እገድላለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፬ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ጥለዋልና ፥ ትእዛዙንም ፡ አልጠበቁምና ፥ አባቶቻቸውም ፡ የተከተሉት ፡ ሐሰታቸው ፡ አስቶአቸዋልና ፡ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የይሁዳ ፡ ኃጢአት ፡ መቅ

፭ ሠፍቴን ፡ ከማድረግ ፡ አልመለስም ። በይሁዳ ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ እሰድዳለሁ ፥ የኢየሩሳሌምንም ፡ አዳራሾች ፡ ትበላለች ።

፮ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ጻድቁን ፡ ስለ ፡ ብር ፥ ችጋረኛውንም ፡ ስለ ፡ አንድ ፡ ጥንድ ፡ ጫማ ፡ ሸጠውታልና ፡ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የእስራኤል ፡ ኃጢአት ፡ መቅ

፯ ሠፍቴን ፡ ከማድረግ ፡ አልመለስም ። የድሆችን ፡ ራስ ፡ በምድር ፡ ትቢያ ፡ ላይ ፡ ይረግጣሉ ፥ የትሑታንንም ፡ መንገድ ፡ ያጣምማሉ ፤ ቅዱሱንም ፡ ስሜን ፡ ያረክሱ ፡ ዘንድ ፡ አባትና ፡ ልጁ ፡ ወደ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ይገባሉ ፤ በመሠዊያ

፰ ውም ፡ ሁሉ ፡ አጠገብ ፡ ለመያዣነት ፡ በተወሰደው ፡ ልብስ ፡ ላይ ፡ ይተኛሉ ፤ በአምላካቸውም ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ በካሣ ፡ የተወሰደውን ፡

፱ ወይን ፡ ጠጅ ፡ ይጠጣሉ ። እኔ ፡ ግን ፡ ቁመቱ ፡ እንደ ፡ ዝግባ ፡ ቁመት ፥ ብርታቱም ፡ እንደ ፡ ኮምበል ፡ ዛፍ ፡ የነበረውን ፡ አሞራዊውን ፡ ከፊታቸው ፡ አጠፋሁ ፤ ፍሬውንም ፡ ከላዩ ፥ ሥሩንም ፡ ከታቹ ፡ አጠፋሁ ። የአሞራዊውንም ፡

፲ ምድር ፡ ትወርሱ ፡ ዘንድ ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ አወጣኋችሁ ፥ በምድረ ፡ በዳም ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡

፲፩ መራኋችሁ ። ከወንድ ፡ ልጆቻችሁም ፡ ነቢያትን ፥ ከጕበዛዝቶቻችሁም ፡ ናዝራውያንን ፡ አስነሣሁ ፤ እናንተ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡ እንደዚህ ፡ አይደለምን ? ይላል ፡ እግዚአ

፲፪ ብሔር ። እናንተ ፡ ግን ፡ ናዝራውያኑን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ አጠጣችኋቸው ፤ ነቢያቱንም ፦ ትንቢትን ፡ አትናገሩ ፡ ብላችሁ ፡ አዘዛችኋቸው ።

፲፫ እነሆ ፥ ነዶ ፡ የተሞላች ፡ ሰረገላ ፡ እንደምትደቅቅ ፡ እንዲሁ ፡ እደቀድቃችኋለሁ ።

፲፬ ከርዋጪም ፡ ሽሽት ፡ ይጠፋል ፥ ብርቱውም ፡ በብርታቱ ፡ አይበረታም ፥ ኃያሉም ፡ ነፍሱን ፡ አያ

፲፭ ድንም ፤ ቀስተኛውም ፡ አይቆምም ፥ ፈጣኑም ፡ አይድንም ፥ ፈረሰኛውም ፡ ነፍሱን ፡ አያድንም ፤

፲፮ በኃያላኑም ፡ መካከል ፡ ልበ ፡ ሙሉው ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ዕራቁቱን ፡ ሆኖ ፡ ይሸሻል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔር ፡ በእናንተ ፥ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ በወጣሁት ፡ ወገን ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የተናገረውን ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ስሙ ፤

፪ እንዲህም ፡ ብሎአል ፦ እኔ ፡ ከምድር ፡ ወገን ፡ ሁሉ ፡ እናንተን ፡ ብቻችሁን ፡ አውቄአችኋለሁ ፤ ስለዚህ ፡ ስለ ፡ ኃጢአታችሁ ፡ ሁሉ ፡ እበቀላች

፫ ኋለሁ ። በውኑ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ሳይስማሙ ፡

፬ በአንድነት ፡ ይሄዳሉን ? ወይስ ፡ አንበሳ ፡ የሚነጥቀው ፡ ነገር ፡ ሳያገኝ ፡ በጫካ ፡ ውስጥ ፡ ያገሣልን ? ወይስ ፡ የአንበሳ ፡ ደቦል ፡ አንዳች ፡ ሳይዝ ፡ በመደቡ ፡ ሆኖ ፡ ይጮኻልን ? ወይስ ፡

፭ ወፍ ፥ አጥማጅ ፡ ከሌለው ፥ በምድር ፡ ላይ ፡ በወጥመድ ፡ ይያዛልን ? ወይስ ፡ ወስፈንጠር ፡ አን

፮ ዳች ፡ ሳይዝ ፡ ከምድር ፡ ይፈነጠራልን ? ወይስ ፡ በከተማ ፡ ውስጥ ፡ መለከት ፡ ሲነፋ ፡ ሕዝቡ ፡ አይፈራምን ? ወይስ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ በከተማ ፡ ላይ ፡ የመጣ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያደረገው ፡ እግዚአ

፯ ብሔር ፡ አይደለምን ? በእውነት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምሥጢሩን ፡ ለባሪያዎቹ ፡ ለነቢያት ፡

፰ ካልነገረ ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ አያደርግም ። አንበሳው ፡ አገሣ ፤ የማይፈራ ፡ ማን ፡ ነው ? ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናገረ ፤ ትንቢት ፡ የማይናገር ፡ ማን ፡ ነው ?

፱ በአዛጦን ፡ አዳራሾችና ፡ በግብጽ ፡ ምድር ፡

አዳራሾች ፡ አውሩና ፡— በሰማርያ ፡ ተራሮች ፡ ላይ ፡ ተሰብሰቡ ፥ በውስጥዋም ፡ የሆነውን ፡ ታላቁን ፡ ውከታ ፥ በመካከልዋም ፡ ያለውን ፡ ግፍ ፡ ተመልከቱ ፡ በሉ ። ፲ ግፍንና ፡ ቅሚያን ፡ በአዳራሾቻቸው ፡ የሚያከማቹት ፡ ቅን ፡ ነገርን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አያውቁም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፲፩ ስለዚህ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በምድሪቱ ፡ ዙሪያ ፡ ጠላት ፡ ይመጣል ፤ ብርታትሽንም ፡ ከአንቺ ፡ ያወርዳል ፥ ፲፪ አዳራሾችሽም ፡ ይበዘበዛሉ ። እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እረኛ ፡ ከአንበሳ ፡ አፍ ፡ ሁለት ፡ እግርን ፡ ወይም ፡ የጆሮን ፡ ጫፍ ፡ እንደሚያድን ፥ እንዲሁ ፡ በሰማርያ ፡ በአልጋ ፡ ማዕዘን ፥ በደማስቆም ፡ በምንጣፍ ፡ ላይ ፡ የተቀመጡት ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ይድናሉ ።

፲፫ ስሙ ፥ በያዕቆብም ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ መስክሩ ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ፲፬ እስራኤልን ፡ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ በምበቀልበት ፡ ቀን ፡ የቤቴልን ፡ መሠዊያዎች ፡ ደግሞ ፡ እበቀላለሁ ፤ የመሠዊያው ፡ ቀንዶች ፡ ይሰበራሉ ፥ ወደ ፡ ምድርም ፡ ይወድቃሉ ። ፲፭ የክረምቱንና ፡ የበጋውን ፡ ቤት ፡ እመታለሁ ፤ በዝሆንም ፡ ጥርስ ፡ የተለበጡት ፡ ቤቶች ፡ ይጠፋሉ ፥ ታላላቆችም ፡ ቤቶች ፡ ይፈርሳሉ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ በሰማርያ ፡ ተራራ ፡ የምትኖሩ ፥ ድሆችንም ፡ የምትበድሉ ፥ ችጋረኞችንም ፡ የምታስጨንቁ ፥ ጌቶቻቸውንም ፡— አምጡ ፡ እንጠጣ ፡ የምትሉ ፡ እናንተ ፡ የባሳን ፡ ላሞች ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ ቃል ፡ ስሙ ። ፪ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡— እናንተን ፡ በሰልፍ ፡ ዕቃ ፥ ቅሬታችሁንም ፡ በመቃጥን ፡ የሚወስዱበት ፡ ቀን ፥ እነሆ ፥ በላያችሁ ፡ ይመጣል ፡ ብሎ ፡ በቅዱስነቱ ፡ ምሎአል ። ፫ እያንዳንዳችሁ ፡ በየፊታችሁ ፡ በተነደለ ፡ ስፍራ ፡ ትወጣላችሁ ፤ በሬማንም ፡ ትጣላላችሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፬ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ ወድዳችኋልና ፡ ወደ ፡ ቤቴል ፡ ኑና ፡ ኃጢአትን ፡ ሥሩ ፤ ወደ ፡ ጌልገላ ፡ ኑና ፡ ኃጢአትን ፡ አብዙ ፤ በየማለዳውም ፡ መሥዋዕታችሁን ፥ በየሦስተኛውም ፡ ፭ ቀን ፡ አሥራታችሁን ፡ አቅርቡ ፤ እርሾ ፡ ካለበትም ፡ የምስጋናውን ፡ መሥዋዕት ፡ አቅርቡ ፥ በፈቃዳችሁም ፡ የምታቀርቡትን ፡ አውጁና ፡ አውሩ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፮ በከተማችሁ ፡ ሁሉ ፡ ጥርስን ፡ ማጥራት ፥ በስፍራችሁም ፡ ሁሉ ፡ እንጀራን ፡ ማጣት ፡ ሰጠኋችሁ ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አልተመለሳችሁም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፯ መከር ፡ ሳይደርስ ፡ ገና ፡ ከሦስት ፡ ወር ፡ በፊት ፡ ዝናብ ፡ ከለከልኋችሁ ፤ በአንድም ፡ ከተማ ፡ ላይ ፡ አዘነብሁ ፥ በሌላውም ፡ ከተማ ፡ ላይ ፡ እንዳይዘንብ ፡ አደረግሁ ፤ በአንድ ፡ ወገን ፡ ዘነበ ፥ ያልዘነበበትም ፡ ወገን ፡ ደረቀ ። ፰ የሁለት ፡ ወይም ፡ የሦስት ፡ ከተሞች ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ አንዲት ፡ ከተማ ፡ ውኃ ፡ ይጠጡ ፡ ዘንድ ፡ ሄዱ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አልረኩም ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አልተመለሳችሁም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፱ በዋግና ፡ በአረማሞ ፡ መታኋችሁ ፤ የአታክልቶቻችሁንም ፡ ብዛት ፡ ወይኖቻችሁንም ፡ በለሶቻችሁንም ፡ ወይራዎቻችሁንም ፡ ተምች ፡ በልቶአል ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አልተመለሳችሁም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፲ በግብጽ ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡ ቸነፈርን ፡ ሰደድሁባችሁ ፤ ጕበዛዝቶቻችሁን ፡ በሰይፍ ፡ ገደልሁ ፥ ፈረሶቻችሁንም ፡ አስማረክሁ ፤ የሰፈራችሁንም ፡ ግማት ፡ ወደ ፡ አፍንጫችሁ ፡ አወጣሁ ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አልተመለሳችሁም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ፲፩ ሰዶምንና ፡ ገሞራን ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ገለበጣቸው ፥ እንዲሁ ፡ ገለበጥኋችሁ ፥ እናንተም ፡ ከእሳት ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ ተነጠቀ ፡ ትንታግ ፡ ሆናችሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አልተመለሳችሁም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፲፪ ስለዚህ ፥ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ እንደዚህ ፡ አደርግብሃለሁ ፤ እስራኤልም ፡ ሆይ ፥ እንደዚህ ፡ ስለማደርግብህ ፡ አምላክህን ፡ ለመገናኘት ፡ ተዘጋጅ ። ፲፫ እነሆ ፥ ተራሮችን ፡ የሠራ ፥ ነፋስንም ፡ የፈጠረ ፥ የልቡንም ፡ አሳብ ፡ ለሰው ፡ የሚነግር ፥ ንጋትን ፡ ጨለማ ፡ የሚያደርግ ፥ በምድርም ፡ ከፍታዎች ፡ ላይ ፡ የሚረግጥ ፥ ስሙ ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ለሙሾ ፡ የማነሣውን ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ስሙ ። ፪ የእስራኤል ፡ ድንግል ፡ ወደቀች ፥ ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ አትነሣም ፤ በምድርዋ ፡ ላይ ፡ ተጣለች ፥ የሚያስነሣትም ፡ የለም ። ፫ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— ሺህ ፡ ከሚወጣበት ፡ ከተማ ፡ መቶ ፡ ይቀርላታል ፥ መቶም ፡ ከሚወጣበት ፡ ከተማ ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ አሥር ፡ ይቀርላታል ።

፬ እግዚአብሔርም ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— እኔን ፡ ፈልጉ ፥ በሕይወትም ፡ ትኖራላችሁ ፤ ፭ ነገር ፡ ግን ፡ ጌልገላ ፡ ፈጽሞ ፡ ትማረካለችና ፥ ቤቴልም ፡ ከንቱ ፡ ትሆናለችና ፡ ቤቴልን ፡ አትፈልጉ ፥ ወደ ፡ ጌልገላም ፡ አትግቡ ፥ ወደ ፡ ቤርሳቤህም ፡ አትለፉ ። ፮ በዮሴፍ ፡ ቤት ፡ እሳት ፡ እንዳትቃጠል ፥ በቤቴል ፡ የሚያጠፋትም ፡ ሳይኖር ፡ እንዳትበላ ፥ እግዚአብሔርን ፡ ፈልጉ ፥ በሕይወትም ፡ ትኖራላችሁ ። ፯ ፍርድን ፡ ወደ ፡ እሬት ፡ የምትለውጡ ፥ ጽድቅንም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የምትጥሉ ፡ እናንተ ፡ ሆይ ፥ ፰ ሰባቱን ፡ ከዋክብትና ፡ አሪዮን ፡ የተባለውን ፡ ኮከብ ፡ የፈጠረውን ፥ የሞትን ፡ ጥላ ፡ ወደ ፡ ንጋት ፡ የሚለውጠውን ፥ ቀኑንም ፡ በሌሊት ፡ የሚያጨልመውን ፥ የባሕሩንም ፡

ውኆች፡ጠርቶ፡በምድር፡ፊት፡ላይ፡የሚያ
፱፤ ፈስሳቸውን÷ አምባውም፡እንዲፈርስ፡በብ
ርቱ፡ላይ፡የድንገት፡ጥፋት፡የሚያመጣውን፡
ፈልጉ፤ ስሙ፡እግዚአብሔር፡ነው።
፲፤ በበሩ፡አደባባይ፡የሚገሥጸውን፡ጠሉ÷
፲፩፤ እውነትም፡የሚናገረውን፡ተጸየፉ። ድሀው
ንም፡ደብድባችኋልና÷የስንዴውንም፡ቀረጥ፡
ከእርሱ፡ወስዳችኋልና፡ከተጠረበ፡ድንጋይ፡
ቤቶችን፡ሠርታችኋል÷ነገር፡ግን፡አትቀመ
ጡባቸውም፤ ያማሩ፡የወይን፡ቦታዎች፡ተክ
ላችኋል÷ነገር፡ግን፡ከወይን፡ጠጃቸው፡
፲፪፤ አትጠጡም። ጻድቁን፡የምታስጨንቁ÷ጉቦ
ንም፡የምትቀበሉ÷በበሩም፡አደባባይ፡የች
ጋረኛውን፡ፍርድ፡የምታጣምሙ፡እናንተ፡
ሆይ÷በደላችሁ፡እንዴት፡እንደ፡በዛ÷ኃጢ
አታችሁም፡እንዴት፡እንደ፡ጸና፡እኔ፡አው
፲፫፤ ቃለሁና። ስለዚህ፡ክፉ፡ዘመን፡ነውና፡በዚያ፡
ዘመን፡አስተዋይ፡የሚሆን፡ዝም፡ይላል።
፲፬፤ በሕይወት፡ትኖሩ፡ዘንድ፡መልካሙን፡እንጂ፡
ክፉውን፡አትፈልጉ፤ እንዲሁም፡እናንተ፡
እንደ፡ተናገራችሁ፡የሠራዊት፡አምላክ፡እግዚ
፲፭፤ አብሔር፡ከእናንተ፡ጋር፡ይሆናል። ክፉውን፡
ጥሉ÷መልካሙንም፡ውደዱ÷በበሩም፡አደ
ባባይ፡ፍርድን፡አጽኑ፤ ምናልባት፡የሠራ
ዊት፡አምላክ፡እግዚአብሔር፡ለዮሴፍ፡
ቅሬታ፡ይራራ፡ይሆናል።
፲፮፤ ስለዚህ፡ጌታ፡የሠራዊት፡አምላክ፡እግዚ
አብሔር፡እንዲህ፡ይላል፡— በየአደባባዩ፡
ሁሉ፡ላይ፡ዋይታ፡ይሆናል፤ በየመንገዱም፡
ሁሉ፡ላይ፡ወዮ፡ወዮ፡ይባላል፤ ገበሬዎቹም፡
ወደ፡ልቅሶ÷አልቃሾቹም፡ወደ፡ዋይታ፡
፲፯፤ ይጠራሉ። በመካከልህ፡አልፋለሁና፡በወ
ይኑ፡ቦታ፡ሁሉ፡ልቅሶ፡ይሆናል÷ይላል፡
እግዚአብሔር።
፲፰፤ የእግዚአብሔርን፡ቀን፡ለምትፈልጉ፡ወዮ
ላችሁ! የእግዚአብሔርን፡ቀን፡ለምን፡ትፈ
ልጋላችሁ? ጨለማ፡ነው፡እንጂ፡ብርሃን፡
፲፱፤ አይደለም። ከአንበሳ፡ፊት፡እንደ፡ሸሸ፡
ድብም፡እንዳገኘው፡ሰው÷ወይም፡ወደ፡
ቤት፡ገብቶ፡እጁን፡በግድግዳ፡ላይ፡እንዳስ
ደገፈና፡እባብ፡እንደ፡ነደፈው፡ሰው፡ነው።
፳፤ የእግዚአብሔር፡ቀን፡ብርሃን፡ሳይሆን፡ጨለማ፡
አይደለምን? ፀዳል፡የሌለውም፡ድቅድቅ፡
ጨለማ፡አይደለምን?
፳፩፤ ዓመት፡በዓላችሁን፡ጠልቼዋለሁ፡ተጸይፌ
ውማለሁ፤ የተቀደሰውም፡ጉባኤአችሁ፡ደስ፡
፳፪፤ አያሰኘኝም። የሚቃጠለውን፡መሥዋዕታች
ሁና፡የእህሉን፡ቍርባናችሁን፡ብታቀርቡል
ኝም፡እንኳ፡አልቀበለውም፤ ለምስጋና፡መሥ
ዋዕት፡የምታቀርቡልኝን፡የሰቡትን፡እንስ
፳፫፤ ሶች፡አልመለከትም። የዝማሬህንም፡ጩኸት፡
ከእኔ፡ዘንድ፡አርቅ፤ የመሰንቆህንም፡ዜማ፡
፳፬፤ አላደምጥም። ነገር፡ግን፡ፍርድ፡እንደ፡ውኃ÷
ጽድቅም፡እንደማይደርቅ፡ፈሳሽ፡ይፍሰስ።

፳፭፤ የእስራኤል፡ቤት፡ሆይ÷በውኑ፡በምድረ፡
በዳ፡አርባ፡ዓመት፡ሙሉ፡መሥዋዕትንና፡
፳፮፤ ቍርባንን፡አቅርባችሁልኛልን? ለራሳችሁም፡
የሠራችኋቸውን፡ምስሎች÷የሞሎክን፡ድን
ኳንና፡የአምላካችሁን፡የሬፋን፡ኮከብ፡አንሣ
፳፯፤ ችሁ። ስለዚህ፡ከደማስቆ፡ወደዚያ፡አስማርካ
ችኋለሁ÷ ይላል፡ስሙ፡የሠራዊት፡አምላክ፡
የተባለ፡እግዚአብሔር።

## ምዕራፍ፡፮።

፩፤ በጽዮን፡ላሉ፡ዓለመኞች÷በሰማርያም፡
ተራራ፡ላይ፡ተዘልለው፡ለተቀመጡ÷የእስ
ራኤልም፡ቤት፡ወደ፡እነርሱ፡ለመጡባቸው፡
፪፤ ለአሕዛብ፡አለቆች፡ወዮላቸው! ወደ፡ካልኔ፡
አልፋችሁ፡ተመልከቱ፤ ከዚያም፡ወደ፡ታላ
ቂቱ፡ሐማት፡ሂዱ፤ ከዚያም፡ወደ፡ፍልስጥ
ኤም፡ጌት፡ውረዱ፤ እነርሱ፡ከእነዚህ፡መን
ግሥታት፡ይሻላሉን? ወይስ፡ድንበራቸው፡
፫፤ ከድንበራችሁ፡ይሰፋልን? ክፉውን፡ቀን፡
ከእናንተ፡ለምታርቁ÷የግፍንም፡ወንበር፡
፬፤ ለምታቀርቡ÷ ከዝሆን፡ጥርስ፡በተሠራ፡
አልጋ፡ላይ፡ለምትተኙ÷በምንጣፋችሁም፡
ላይ፡ተደላድላችሁ፡ለምትቀመጡ÷ከበጎችም፡
መንጋ፡ጠቦትን፡ከጋጥም፡ውስጥ፡ጥጃን፡
፭፤ ለምትበሉ÷ በመሰንቆም፡ድምፅ፡ለምትን
ጫጩ÷እንደ፡ዳዊትም፡የዜማን፡ዕቃ፡
፮፤ ለምታዘጋጁ÷ በፋጋ፡የወይን፡ጠጅ፡ለምት
ጠጡ÷እጅግ፡በማረ፡ሽቱም፡ለምትቀቡ÷
ስለ፡ዮሴፍ፡መከራ፡ግን፡ለማታዝኑ፡ለእና
ንተ፡ወዮላችሁ!
፯፤ ስለዚህ፡በምርኮ፡መጀመሪያ፡ይማረካሉ÷
ተደላድለው፡ከተቀመጡትም፡ዘንድ፡ዘፈን፡
፰፤ ይርቃል። ጌታ፡እግዚአብሔር፡— የያዕቆብን፡
ትዕቢት፡ተጸይፌአለሁ÷አዳራሾቹንም፡ጠል
ቻለሁ፤ ስለዚህ፡ከተማይቱንና፡የሚኖሩብ
ትን፡ሁሉ፡አሳልፌ፡እሰጣለሁ፡ብሎ፡በራሱ፡
ምሎአል÷ይላል፡የሠራዊት፡አምላክ፡እግ
፱፤ ዚአብሔር። እንዲህም፡ይሆናል፤ አሥር፡
ሰዎች፡በአንድ፡ቤት፡ውስጥ፡ቢቀሩ፡እነ
፲፤ ርሱ፡ይሞታሉ። አጥንቱንም፡ከቤቱ፡ያወጡ፡
ዘንድ፡የሰው፡ዘመድና፡አቃጣዩ፡በነሡት፡
ጊዜ÷በቤቱም፡ውስጥ፡ያለውን፡— እስከ፡
አሁን፡ድረስ፡ገና፡ሰው፡በአንተ፡ዘንድ፡
አለን? ባለው፡ጊዜ÷እርሱም፡— ማንም፡
የለም፡ባለ፡ጊዜ፤ ያን፡ጊዜ፡— የእግዚአብ
ሔርን፡ስም፡እንጠራ፡ዘንድ፡አይገባንምና፡
፲፩፤ ዝም፡በል፡ይለዋል። እነሆም÷እግዚአብ
ሔር፡ያዝዛል፤ ታላቁንም፡ቤት፡በማፍረስ÷
ታናሹንም፡ቤት፡በመሰባበር፡ይመታል።
፲፪፤ ፲፫፤ ፍርድን፡ወደ፡ሐሞት÷የጽድቅንም፡ፍሬ፡
ወደ፡እሬት፡የለወጣችሁ÷በከንቱም፡ነገር፡
ደስ፡የሚላችሁ፡— በኃይላችን፡ቀንድ፡የወ
ሰድን፡አይደለምን? የምትሉ÷እናንተ፡ሆይ÷
በውኑ፡ፈረሶች፡በጭንጫ፡ላይ፡ይጋልባሉን?

ወይስ ፡ በሬዎች ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ ያርሳሉን ? ፲፬፤ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ እነሆ ÷ እኔ ፡ ሕዝብን ፡ አስነሣባችኋለሁ ÷ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፤ እነርሱም ፡ ከሐማት ፡ መግቢያ ፡ጀምረው ፡ እስከ ፡ ዓረብ ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ፡ ያስጨንቋችኋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አሳየኝ ፤ እነሆም ÷ የኋለኛው ፡ ሣር ፡ በሚበቅልበት ፡ መጀመሪያ ፡ ላይ ፡ አንበጣን ፡ ፈጠረ ፤ እነሆም ÷ ከንጉሡ ፡ አጨዳ ፡ በኋላ ፡ የበቀለ ፡ የገቦ ፡ ነበረ ። ፪፤ የምድሩንም ፡ ሣር ፡ በልተው ፡ ከጨረሱ ፡ በኋላ ÷ እኔ ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ÷ ይቅር ፡ እንድትል ፡ እለምንሃለሁ ፤ ያዕቆብ ፡ ታናሽ ፡ ፫፤ ነውና ፡ እንዴት ፡ ይቆማል ? አልሁ ። እግዚአብሔርም ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ተጸጸተ ፤ ይህ ፡ አይሆንም ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፬፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ አሳየኝ ፤ እነሆም ÷ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእሳት ፡ ለመፍረድ ፡ ጠራ ፤ እርስዋም ፡ ታላቁን ፡ ቀላይና ፡ ፭፤ ምድርን ፡ በላች ። እኔም ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ÷ እንድትተው ፡ እለምንሃለሁ ፤ ያዕቆብ ፡ ታናሽ ፡ ነውና ፡ እንዴት ፡ ይቆማል ? ፮፤ አልሁ ። እግዚአብሔርም ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ተጸጸተ ፤ ይህ ፡ ደግሞ ፡ አይሆንም ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፯፤ እንዲህም ፡ አሳየኝ ፤ እነሆም ÷ ጌታ ፡ ቱንቢውን ፡ ይዞ ፡ በቱንቢ ፡ በተሠራ ፡ ቅጥር ፡ ላይ ፡ ፰፤ ቆሞ ፡ ነበር ። እግዚአብሔርም ፦ አሞጽ ፡ ሆይ ÷ የምታየው ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለኝ ። እኔም ፦ ቱንቢ ፡ ነው ፡ አልሁ ። ጌታም ፦ እነሆ ÷ በሕዝቤ ፡ በእስራኤል ፡ መካከል ፡ ቱንቢ ፡ አደርጋለሁ ፤ ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ ደግሞ ፡ አላ ፱፤ ልፋቸውም ፤ የይስሐቅም ፡ የኮረብታው ፡ መስገጃዎች ፡ ይፈርሳሉ ÷ የእስራኤልም ፡ መቅደሶች ፡ ባድማ ፡ ይሆናሉ ፤ በኢዮርብዓምም ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ በሰይፍ ፡ እነሣለሁ ፡ አለ ።

፲፤፲፩፤ የቤቴልም ፡ ካህን ፡ አሜስያስ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ኢዮርብዓም ፡ ልኮ ፦ አሞጽ ፦ ኢዮርብዓም ፡ በሰይፍ ፡ ይሞታል ÷ እስራኤልም ፡ ከአገሩ ፡ ተማርኮ ፡ ይሄዳል ፡ ብሎ አልና ፡ አሞጽ ፡ በእስራኤል ፡ ቤት ፡ መካከል ፡ ዐምፆብሃል ፤ ምድሪቱም ፡ ቃሉን ፡ ሁሉ ፡ ልት ፲፪፤ ሸከም ፡ አትችልም ፡ አለ ። አሜስያስም ፡ አሞጽን ፦ ባለ ፡ ራእዩ ፡ ሆይ ÷ ሂድ ፡ ወደ ፡ ይሁዳም ፡ ምድር ፡ ሽሽ ÷ በዚያም ፡ እንጀራን ፡ ብላ ÷ ፲፫፤ በዚያም ፡ ትንቢትን ፡ ተናገር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ቤቴል ፡ የንጉሥ ፡ መቅደስና ፡ የመንግሥት ፡ ቤት ፡ ናትና ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ በዚህ ፡ ደግሞ ፡ ትንቢት ፡ አትናገር ፡ አለው ።

፲፬፤ አሞጽም ፡ መልሶ ፡ አሜስያስን ፡ አለው ፦ እኔ ፡ ላም ፡ ጠባቂና ፡ ወርካ ፡ ለቃሚ ፡ ነኝ ፡ እንጂ ፡ ነቢይ ፡ ወይም ፡ የነቢይ ፡ ልጅ ፡ አይደለሁም ፤ ፲፭፤ እግዚአብሔርም ፡ በጎቼን ፡ ከመከተል ፡ ወሰደኝ ÷ እግዚአብሔርም ፦ ሂድ ÷ ለሕዝቤም ፡ ፲፮፤ ለእስራኤል ፡ ትንቢት ፡ ተናገር ፡ አለኝ ። አሁንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስማ ፤ አንተ ፦ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ትንቢት ፡ አትናገር ÷ በይስሐቅም ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ አትስበክ ፡ ብለሃል ፤ ስለ ፲፯፤ ዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ሚስትህ ፡ በከተማይቱ ፡ ውስጥ ፡ ጋለሞታ ፡ ትሆናለች ÷ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆችህም ፡ በሰይፍ ፡ ይወድቃሉ ÷ ምድርህም ፡ በገመድ ፡ ትከፈላለች ፤ አንተም ፡ በረከሰች ፡ ምድር ፡ ትሞታለህ ÷ እስራኤልም ፡ ከምድሩ ፡ ተማርኮ ፡ ይሄዳል ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አሳየኝ ፤ እነሆም ÷ የቃርሚያ ፡ ፍሬ ፡ የሞላበት ፡ ዕንቅብ ፡ ፪፤ ነበረ ። እርሱም ፦ አሞጽ ፡ ሆይ ÷ የምታየው ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለኝ ። እኔም ፦ የቃርሚያ ፡ ፍሬ ፡ የሞላበት ፡ ዕንቅብ ፡ ነው ፡ አልሁት ። እግዚአብሔርም ፡ አለኝ ፦ ፍጻሜ ፡ በሕዝቤ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ መጥቶአል ፤ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ደግሞ ፡ አላልፋቸውም ። ፫፤ የመቅደሱ ፡ ዝማሬ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ዋይታ ፡ ይሆናል ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ የሰዎችም ፡ ሬሳ ፡ ይበዛል ÷ በስፍራውም ፡ ሁሉ ፡ በዝምታ ፡ ይጣላል ።

፬፤ ችጋረኛውን ፡ የምትውጡ ÷ የአገሩንም ፡ ፭፤ ድሀ ፡ የምታጠፉ ፡ እናንተ ፡ ሆይ ፦ እህልን ፡ እንሸጥ ፡ ዘንድ ፡ መባቻው ፡ መቼ ፡ ያልፋል ? የኢፍ ፡ መስፈሪያውንም ፡ እያሳነስን ÷ ሰቅሉንም ፡ እያበዛን ÷ በሐሰተኛም ፡ ሚዛን ፡ እያታ ፮፤ ለልን ÷ ድሀውን ፡ በብር ፡ ችጋረኛውንም ፡ በአንድ ፡ ጥንድ ፡ ጫማ ፡ እንገዛ ፡ ዘንድ ÷ የስንዴውንም ፡ ግርድ ፡ እንሸጥ ፡ ዘንድ ፡ ስንዴውን ፡ እንድንሸምት ፡ ሰንበት ፡ መቼ ፡ ያልፋል ? የም ፯፤ ትሉ ፡ እናንተ ፡ ሆይ ÷ ይህን ፡ ስሙ ። እግዚአብሔር ፡ በያዕቆብ ፡ ክብር ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ምሎአል ፦ ሥራቸውን ፡ ሁሉ ፡ ለዘላለም ፡ ምንም ፡ ፰፤ አልረሳም ። በውኑ ፡ ምድሪቱ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ አትናወጥምን ? በእርስዋም ፡ የሚኖር ፡ ሁሉ ፡ አያለቅስምን ? ሙላዋም ፡ እንደ ፡ ወንዙ ፡ ትነሣለች ፤ እንደ ፡ ግብጽም ፡ ወንዝ ፡ ትነሣለች ፡ ፱፤ ደግሞም ፡ ትወርዳለች ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ፀሐይ ፡ በቀትር ፡ እንድትገባ ፡ አደርጋለሁ ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ በብርሃንም ፡ ቀን ፡ ምድ ፲፤ ሩን ፡ አጨልማለሁ ። ዓመት ፡ በዓላችሁንም ፡ ወደ ፡ ልቅሶ ÷ ዝማሬአችሁንም ፡ ወደ ፡ ዋይታ ፡ እለውጣለሁ ፤ ማቅንም ፡ በወገብ ፡ ሁሉ ÷ ራስ ፡ መንጨትንም ፡ በሁሉ ፡ ላይ ፡ አመጣለሁ ፤ እንደ ፡ አንድያ ፡ ልጅም ፡ ልቅሶ ÷ ፍጻሜውንም ፡ እንደ ፡ መራራ ፡ ቀን ፡ አደርገዋለሁ ።

፲፩፤ እነሆ ÷ በምድር ፡ ላይ ፡ ራብን ፡ የምሰድድበት ፡ ዘመን ፡ ይመጣል ÷ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ እርሱም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ከመ

ስማት፡እንጂ፡እንጀራን፡ከመራብና፡ውኃን፡
፲፪፤ ከመጠማት፡አይደለም። ከባሕርም፡እስከ፡
ባሕር፡ድረስ÷ከሰሜንም፡እስከ፡ምሥራቅ፡
ድረስ፡ይቅበዘበዛሉ፤የእግዚአብሔርን፡ቃል፡
፲፫፤ ለመሻት፡ይርዋርዋጣሉ÷አያገኙትምም።
በዚያ፡ቀን፡መልካካሞች፡ደናግል፡ጐበዛዝ
፲፬፤ ትም፡በጥም፡ይዝላሉ። በሰማርያ፡ኃጢአት፡
የሚምሉና፦ዳን፡ሆይ÷ሕያው፡አምላክ
ህን! ደግሞ፦ሕያው፡የቤርሳቤህን፡መን
ገድ! ብለው፡የሚሉ÷እነርሱ፡ይወድቃሉ÷
ደግሞም፡አይነሡም።

ምዕራፍ፡፱።

፩፤ ጌታን፡በመሠዊያው፡አጠገብ፡ቆሞ፡አየ
ሁት፤ እርሱም፡እንዲህ፡አለ፦መድረኩቹ፡
ይናወጡ፡ዘንድ፡ጕልላቶቹን፡ምታ÷በራሳ
ቸውም፡ሁሉ፡ላይ፡ሰባብራቸው፤እኔም፡ከእ
ነርሱ፡የቀሩትን፡በሰይፍ፡እገድላለሁ፤የሚ
ሸሽ፡አያመልጥም÷የሚያመልጥም፡አይድ
፪፤ ንም። ወደ፡ሲኦል፡ቢወርዱ፡እጄ፡ከዚያ፡
ታወጣቸዋለች፤ ወደ፡ሰማይም፡ቢወጡ፡
፫፤ ከዚያ፡አወርዳቸዋለሁ፤በቀርሜሎስም፡ራስ፡
ውስጥ፡ቢሸሸጉ፡ፈልጌ፡ከዚያ፡አወጣቸዋ
ለሁ፤በጥልቅ፡ባሕርም፡ውስጥ፡ከዓይኔ፡ቢደ
በቁ፡ከዚያ፡እባቡን፡አዝዛለሁ÷እርሱም፡
፬፤ ይነድፋቸዋል፤ በጠላቶቻቸውም፡ፊት፡ተማ
ርከው፡ቢሄዱ፡ከዚያ፡ሰይፍን፡አዝዛለሁ÷
እርሱም፡ይገድላቸዋል፤ዓይኔንም፡በእነርሱ፡
ላይ፡ለክፉት፡እንጂ፡ለመልካም፡አላደርግም።
፭፤ የሠራዊት፡ጌታ፡እግዚአብሔር፡ምድርን፡
ይዳስሳል፡እርስዋም፡ትቀልጣለች÷የሚኖሩ
ባትም፡ሁሉ፡ያለቅሳሉ፤ሙላዋም፡እንደ፡
ግብጽ፡ወንዝ፡ትነሣለች÷ደግሞም፡እንደ፡
፮፤ ግብጽ፡ወንዝ፡ትወርዳለች። አዳራሹን፡በሰ
ማይ፡የሠራ÷ጠፈሩንም፡በምድር፡ላይ፡የመ
ሠረተ÷የባሕርንም፡ውኃ፡ጠርቶ፡በምድር፡
ፊት፡ላይ፡የሚያፈስሰው፡እርሱ፡ነው፤
ስሙም፡እግዚአብሔር፡ነው።
፯፤ የእስራኤል፡ልጆች፡ሆይ÷እናንተ፡ለእኔ፡
እንደ፡ኢትዮጵያ፡ልጆች፡አይደላችሁምን?
ይላል፡እግዚአብሔር። እስራኤልን፡ከግ
ብጽ፡ምድር÷ፍልስጥኤማውያንንም፡ከከፍ
ቶር÷ሶርያውያንንም፡ከቂር፡አላወጣሁምን?
፰፤ እነሆ÷የጌታ፡የእግዚአብሔር፡ዓይኖች፡በኃ
ጢአተኛ፡መንግሥት፡ላይ፡ናቸው÷ከምድ
ርም፡ፊት፡አጠፋታለሁ፤ ነገር፡ግን፡የያዕቆ
ብን፡ቤት፡ፈጽሜ፡አላጠፋም÷ይላል፡እግ
፱፤ ዚአብሔር። እነሆ÷አዝዛለሁ÷እህልም፡በወ
ንፊት፡እንዲነፋ፡የእስራኤልን፡ቤት፡በአሕ
ዛብ፡ሁሉ፡መካከል፡እነፋለሁ፤ነገር፡ግን፡
አንዲት፡ቅንጣት፡በምድር፡ላይ፡አትወድ
፲፤ ቅም። ክፉው፡ነገር፡አይደርስብንም÷አያገ
ኘንምም፡የሚሉ፡የሕዝቤ፡ኃጢአተኞች፡
ሁሉ፡በሰይፍ፡ይሞታሉ።
፲፩፤ በዚያ፡ቀን፡የወደቀችውን፡የዳዊትን፡ድን
ኳን፡አነሣለሁ÷የተናደውንም፡ቅጥርዋን፡
እጠግናለሁ፤የፈረሰውንም፡አድሳለሁ÷እንደ፡
፲፪፤ ቀደመውም፡ዘመን፡እሠራታለሁ፤ ይኸውም፡
የኤዶምያስን፡ቅሬታ÷ስሜም፡የተጠራባቸ
ውን፡አሕዛብን፡ሁሉ፡ይወርሱ፡ዘንድ፡ነው÷
ይላል፡ይህን፡የሚያደርግ፡እግዚአብሔር።
፲፫፤ እነሆ÷አራሹ፡አጫጁን÷ወይን፡ጠማቂ
ውም፡ዘሪውን፡የሚያገኝበት፡ወራት፡ይመ
ጣል÷ይላል፡እግዚአብሔር፤ ተራሮችም፡
በተሀውን፡የወይን፡ጠጅ፡ያንጠባጥባሉ÷
፲፬፤ ኮረብቶችም፡ሁሉ፡ይቀልጣሉ። የሕዝቤን፡
የእስራኤልን፡ምርኮ፡እመልሳለሁ÷የፈረሱ
ትንም፡ከተሞች፡ሠርተው፡ይቀመጡባቸ
ዋል፤ ወይንንም፡ይተክላሉ÷የወይን፡ጠጁ
ንም፡ይጠጣሉ፤ አታክልትንም፡ያበጃሉ÷
፲፭፤ ፍሬውንም፡ይበላሉ። በምድራቸውም፡እተ
ክላቸዋለሁ÷ከእንግዲህም፡ወዲህ፡ከሰጠኋ
ቸው፡ከምድራቸው፡አይነቀሉም÷ይላል፡
አምላክህ፡እግዚአብሔር።

# ትንቢተ፡ሚክያስ።

ምዕራፍ፡፩።

፩፤ በይሁዳ፡ነገሥታት፡በኢዮአታምና፡በአ
ካዝ፡በሕዝቅያስም፡ዘመን፡ወደ፡ሞሬታ
ዊው፡ወደ፡ሚክያስ፡የመጣው÷ስለ፡ሰማር
ያና፡ስለ፡ኢየሩሳሌም፡ያየው÷የእግዚአብ
፪፤ ሔር፡ቃል፡ይህ፡ነው። እናንተ፡አሕዛብ፡
ሁሉ÷ስሙ፤ ምድርም፡ሙላዋም፡ታድምጥ፤
ጌታ፡እግዚአብሔርም÷እርሱም፡በቅዱስ፡
መቅደሱ፡የሆነ፡ጌታ÷ይመስክርባችሁ።
፫፤ እነሆ÷እግዚአብሔር፡ከስፍራው፡ይወጣል÷
ወርዶም፡በምድር፡ከፍታዎች፡ላይ፡ይረግ
፬፤ ጣል። ተራሮችም፡በእሳት፡ፊት፡እንዳለ፡
ሰም÷በገደልም፡ወርዶ፡እንደሚፈስስ፡
ውኃ÷በበታቹ፡ይቀልጣሉ÷ሸለቆችም፡ይሰ
፭፤ ነጠቃሉ። ይህ፡ሁሉ፡ስለ፡ያዕቆብ፡በደ
ልና፡ስለ፡እስራኤል፡ቤት፡ኃጢአት፡ነው።
የያዕቆብም፡በደል፡ምንድር፡ነው? ሰማርያ፡
አይደለችምን? የይሁዳስ፡የኮረብታው፡መስ
ገጃ፡ምንድር፡ነው? ኢየሩሳሌም፡አይደለች
፮፤ ምን? ስለዚህ፡ሰማርያን፡በሜዳ፡እንደሚገኝ፡
የድንጋይ፡ክምር÷ወይን፡እንደሚተከልበ
ትም፡ስፍራ፡አደርጋታለሁ፤ ድንጋዮችዋ
ንም፡ወደ፡ሸለቆ፡እወረውራለሁ÷መሠረቶ

፯ ችዋንም ፡ እገልጣለሁ ። የተቀረጹትም ፡ ምስሎ
ችዋ ፡ ይደቅቃሉ ፥ በግልሙትና ፡ ያገኘችው ፡
ዋጋ ፡ ሁሉ ፡ በእሳት ፡ ይቃጠላል ፥ ጣዖታትዋ
ንም ፡ ሁሉ ፡ አጠፋለሁ ፤ በግልሙትና ፡ ዋጋ ፡
ሰበሰበቻቸው ፥ ወደ ፡ ግልሙትናም ፡ ዋጋ ፡
፰ ይመለሳሉና ። ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ዋይ ፡ ብላ ፡ ታለ
ቅሳለች ፥ በዶ ፡ እግርዋንና ፡ ዕራቁትዋን ፡ ሆና ፡
ትሄዳለች ፤ እንደ ፡ ቀበሮ ፡ ታለቅሳለች ፥ እንደ ፡
፱ ሰጐንም ፡ ዋይ ፡ ትላለች ፤ ቍስልዋ ፡ የማይፈ
ወስ ፡ ነውና ፤ እስከ ፡ ይሁዳም ፡ ደርሶአልና ፥
ወደ ፡ ሕዝቤም ፡ በር ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ቀር
፲ ቦአልና ። በጌት ፡ ላይ ፡ አታውሩ ፤ በአክ ፡ ላይ ፡
እንባን ፡ አታድርጉ ፤ በቤትዓፍራ ፡ በትቢያ ፡
፲፩ ላይ ፡ ተንከባለሉ ። በሻፊር ፡ የምትቀመጪ ፡
ሆይ ፥ በዕራቁትነትሽና ፡ በእፍረት ፡ እለፊ ፤
በጸዓናን ፡ የምትቀመጠው ፡ አልወጣችም ፤ የቤ
ትኤጼል ፡ ልቅሶ ፡ ከእናንተ ፡ ዘንድ ፡ መኖርያ
፲፪ ውን ፡ ይወስዳል ። ክፉ ፡ ነገር ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ዘንድ ፡ እስከ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በር ፡ ድረስ ፡ ወር
ዶአልና ፡ በማሮት ፡ የምትቀመጠው ፡ በጎነትን ፡
፲፫ ትጠባበቃለች ። በለኪሶ ፡ የምትቀመጪ ፡ ሆይ ፥
ሰረገላውን ፡ ለፈረስ ፡ እሰሪ ፤ እርስዋ ፡ ለጽዮን ፡
ሴት ፡ ልጅ ፡ የኃጢአት ፡ መጀመሪያ ፡ ነበረች ፤
የእስራኤል ፡ በደል ፡ በአንቺ ፡ ዘንድ ፡ ተገኝቶ
፲፬ አልና ። ስለዚህ ፡ ትሎት ፡ ለሞሬሼትጌት ፡ ትሰ
ጪአለሽ ፤ የአክዚብ ፡ ቤቶች ፡ ለእስራኤል ፡
፲፭ ነገሥታት ፡ አታላይ ፡ ይሆናሉ ። በመሪሳ ፡ የም
ትቀመጪ ፡ ሆይ ፥ ወራሽ ፡ አመጣብሻለሁ ፤ የእ
ስራኤል ፡ ክብር ፡ ወደ ፡ ዓዶላም ፡ ይመጣል ።
፲፮ ተማርከው ፡ ከአንቺ ፡ ዘንድ ፡ ወጥተዋልና ፡
ስለ ፡ ተድላሽ ፡ ልጆች ፡ ራስሽን ፡ ንጪ ፥ ጠጕ
ርሽንም ፡ ተቈረጪ ፤ ቡሃነትሽንም ፡ እንደ ፡
ንስር ፡ አስፊ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ በመኝታቸው ፡ ላይ ፡ በደልን ፡ ለሚያስቡ ፡
ክፋትንም ፡ ለሚያደርጉ ፡ ወዮላቸው ! ኃይል ፡
በእጃቸው ፡ ነውና ፡ ሲነጋ ፡ ይፈጽሙታል ።
፪ በእርሻው ፡ ላይ ፡ ይመኛሉ ፥ በግዴታም ፡ ይይ
ዙታል ፤ በቤቶችም ፡ ላይ ፡ ይመኛሉ ፥ ይወስ
ዱአቸውማል ፤ ሰውንና ፡ ቤቱን ፥ ሰውንና ፡
፫ ርስቱንም ፡ ይነጥቃሉ ። ስለዚህ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እነሆ ፥ በዚህ ፡ ወገን ፡
ላይ ፡ በክፉ ፡ አስባለሁ ፥ ከዚያም ፡ አንገታች
ሁን ፡ አታነሡም ፤ ዘመኑም ፡ ክፉ ፡ ነውና ፡ ቀጥ ፡
፬ ብላችሁ ፡ አትሄዱም ። በዚያ ፡ ቀን ፡ በምሳሌ ፡
ይመስሉባችኋል ፥ በጽኑ ፡ ልቅሶም ፡ ያለቅሱላ
ችኋል ፤ እነርሱም ፦ ፈጽመን ፡ ጠፍተናል ፤
የሕዝቤን ፡ እድል ፡ ፈንታ ፡ ይሰፍራል ፥ እርሱ
ንም ፡ የሚከለክል ፡ የለም ፤ እርሻችንን ፡ ለዓመ
፭ ፀኞች ፡ ይከፍላል ፡ ይላሉ ። ስለዚህ ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ ጉባኤ ፡ መካከል ፡ በዕጣ ፡ ገመድ ፡
የሚጥል ፡ አይኖርህም ።
፮ ትንቢት ፡ አትናገሩ ፡ብለው ፡ ይናገራሉ ፤
በእነዚህ ፡ ላይ ፡ ትንቢት ፡ አይናገሩም ፥ ስድ
፯ ብም ፡ አይርቅም ። የያዕቆብ ፡ ቤት ፡ የተባልህ ፡
ሆይ ፥ በውኑ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ የማ
ይታገሥ ፡ ነውን ? ወይስ ፡ ሥራው ፡ እንደዚች ፡
ናትን ? ቃሌስ ፡ በቅን ፡ ለሚሄድ ፡ በጎነት ፡ አያ
፰ ደርግምን ? ነገር ፡ ግን ፡ ከቅርብ ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡
ሕዝቤ ፡ እንደ ፡ ጠላት ፡ ሆኖ ፡ ተነሥቶአል ፤
ቀሚስንና ፡ መጐናጸፊያን ፡ ገፈፋችሁ ፤ ሳይፈ
ሩም ፤ የሚያልፉትን ፡ ከሰልፍ ፡ እንደሚመለሱ ፡
፱ አደረጋችኋቸው ። የሕዝቤንም ፡ ሴቶች ፡ ከተ
ሸለሙ ፡ ቤቶቻቸው ፡ አሳደዳችኋቸው ፤ ከሕፃ
ናቶቻቸውም ፡ ክብሬን ፡ ለዘላለም ፡ ወሰዳችሁ ።
፲ በዚህ ፡ ዕረፍት ፡ የላችሁምና ፡ ተነሥታችሁ ፡
ሂዱ ፤ በርኵሰት ፡ ምክንያት ፡ ክፉ ፡ ጥፋት ፡
፲፩ ታጠፋችኋለች ። ነፋስንም ፡ ተከትሎ ፦ ስለ ፡
ወይን ፡ ጠጅና ፡ ስለ ፡ ስካር ፡ ትንቢት ፡ እናገር
ልሃለሁ ፡ ብሎ ፡ ሐሰትን ፡ የሚናገር ፡ ሰው ፡
ቢኖር ፡ እርሱ ፡ ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ነቢይ ፡ ይሆናል ።
፲፪ ያዕቆብ ፡ ሆይ ፥ ሁላንተናህን ፡ ፈጽሞ ፡ እሰበ
ስባለሁ ፥ የእስራኤልንም ፡ ቅሬታ ፡ ፈጽሞ ፡
አከማቻለሁ ፤ እንደ ፡ ባሶራ ፡ በጎችና ፡ እንደ ፡
መንጋ ፡ በማሰማርያቸው ፡ ውስጥ ፡ በአንድነት ፡
አኖራቸዋለሁ ፤ ከሰው ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ድም
፲፫ ፃቸውን ፡ ያሰማሉ ። ሰባሪው ፡ በፊታቸው ፡
ወጥቶአል ፤ እነርሱም ፡ ሰብረው ፡ ወደ ፡ በሩ ፡
አልፈዋል ፥ በእርሱም ፡ በኩል ፡ ወጥተዋል !
ንጉሣቸውም ፡ በፊታቸው ፡ አልፎአል ፥ እግዚ
አብሔርም ፡ በራሳቸው ፡ ላይ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ እንዲህም ፡ አልሁ ፦ የያዕቆብ ፡ አለቆችና ፡
የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ገዦች ፡ ሆይ ፥ እባካችሁ ፡
ስሙኝ ፤ ፍርድን ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ አይገባች
፪ ሁምን ? መልካሙን ፡ ጠልታችኋል ፥ ክፉው
ንም ፡ ወድዳችኋል ፤ ቍርበታቸውን ፡ ገፍፋችኋ
ቸዋል ፥ ሥጋቸውንም ፡ ከአጥንታቸው ፡ ለያይ
፫ ታችኋል ፤ የሕዝቤን ፡ ሥጋ ፡ በልታችኋል ፥
ቍርበታቸውንም ፡ ገፍፋችኋቸዋል ፥ አጥንታ
ቸውንም ፡ ሰብራችኋል ፤ ለአፍላል ፡ እንደሚ
ሆን ፡ ሥጋ ፡ ለድስትም ፡ እንደሚሆን ፡ ሙዳ ፡
፬ ቈራረጣችኋቸው ። የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ይጮኻሉ ፥ እርሱም ፡ አይሰማቸ
ውም ፤ ሥራቸውንም ፡ ክፉ ፡ አድርገዋልና ፡
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ፊቱን ፡ ከእነርሱ ፡ ይሰውራል ።
፭ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቤን ፡ ስለሚያስቱ ፡ ነቢ
ያት ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፤ በጥርሳቸው ፡ ሲነክሱ ፡
በሰላም ፡ ይሰብካሉ ፤ በአፋቸው ፡ ግን ፡ አንዳች ፡
በማይሰጥ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ሰልፍን ፡ ያስቡበታል ።
፮ ስለዚህ ፡ ሌሊት ፡ ይሆንባችኋል ፡ እንጂ ፡ ራእይ ፡
አይሆንላችሁም ፤ ጨለማም ፡ ይሆንባችኋል ፡
እንጂ ፡ አታምዋርቱም ፤ ፀሐይም ፡ በነቢያት ፡
ላይ ፡ ትገባለች ፥ ቀኑም ፡ ይጠቍርባቸዋል ።
፯ ከእግዚአብሔርም ፡ ዘንድ ፡ መልስ ፡ የለምና ፡
ባለ ፡ ራእዮቹ ፡ ያፍራሉ ፥ ምዋርተኞችም ፡ ይዋ

ረዳሉ፤ ሁሉም፡ ከንፈራቸውን፡ ይሸፍናሉ።

፰ እኔ፡ ግን፡ በደሉን፡ ለያዕቆብ፥ ኃጢአቱንም፡ ለእስራኤል፡ እነግር፡ ዘንድ፡ በእግዚአብሔር፡ መንፈስ፡ ኃይልንና፡ ፍርድን፡ ብርታትንም፡ ተሞልቻለሁ።

፱ ፍርድን፡ የምትጠሉ፡ ቅን፡ ነገርንም፡ ሁሉ፡ የምታጣምሙ፡ እናንተ፡ የያዕቆብ፡ ቤት፡ አለቆችና፡ የእስራኤል፡ ቤት፡ ገዦች፡ ሆይ፥ ፲ እባካችሁ፡ ይህን፡ ስሙ። ጽዮንን፡ በደም፥ ፲፩ ኢየሩሳሌምንም፡ በኃጢአት፡ ይሠራሉ። አለቆችዋ፡ በጉቦ፡ ይፈርዳሉ፥ ካህናቶችዋም፡ በዋጋ፡ ያስተምራሉ፥ ነቢያቶችዋም፡ በገንዘብ፡ ያምዋርታሉ፤ ከዚህም፡ ጋር፡—እግዚአብሔር፡ በመካከላችን፡ አይደለምን? ክፉ፡ ነገር፡ ምንም፡ አይመጣብንም፡ እያሉ፡ በእግዚአብሔር፡ ይታመናሉ። ፲፪ ስለዚህ፡ በእናንተ፡ ምክንያት፡ ጽዮን፡ እንደ፡ እርሻ፡ ትታረሳለች፥ ኢየሩሳሌምም፡ የድንጋይ፡ ክምር፡ ትሆናለች፥ የቤቱም፡ ተራራ፡ እንደ፡ ዱር፡ ከፍታ፡ ይሆናል።

## ምዕራፍ፡ ፬።

፩ በመጨረሻውም፡ ዘመን፡ የእግዚአብሔር፡ ቤት፡ ተራራ፡ በተራሮች፡ ራስ፡ ላይ፡ ጸንቶ፡ ይቆማል፥ ከኮረብቶችም፡ በላይ፡ ከፍ፡ ከፍ፡ ይላል፤ ፪ አሕዛብም፡ ወደ፡ እርሱ፡ ይጐርፋሉ። ከጽዮን፡ ሕግ፥ ከኢየሩሳሌምም፡ የእግዚአብሔር፡ ቃል፡ ይወጣልና፡ ብዙዎች፡ አሕዛብ፡ ሄደው፡—ኑ፥ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ ተራራ፥ ወደ፡ ያዕቆብ፡ አምላክ፡ ቤት፡ እንውጣ፤ እርሱም፡ መንገዱን፡ ያስተምረናል፥ በፍለጋውም፡ እንሄዳለን፡ ይላሉ። ፫ በብዙዎችም፡ አሕዛብ፡ መካከል፡ ይፈርዳል፥ በሩቅም፡ ባሉ፡ በብርቱዎች፡ አሕዛብ፡ ላይ፡ ይበይናል፤ ሰይፋቸውንም፡ ማረሻ፥ ጦራቸውንም፡ ማጭድ፡ ለማድረግ፡ ይቀጠቅጣሉ፤ ሕዝብም፡ በሕዝብ፡ ላይ፡ ሰይፍ፡ አያነሣም፡ ከእንግዲህም፡ ወዲህ፡ ሰልፍ፡ አይማሩም። ፬ የሠራዊት፡ ጌታ፡ የእግዚአብሔር፡ አፍም፡ ተናግሮአልና፡ ሰው፡ እያንዳንዱ፡ ከወይኑና፡ ከበለሱ፡ በታች፡ ይቀመጣል፥ የሚያስፈራውም፡ የለም። ፭ ሕዝብም፡ ሁሉ፡ እያንዳንዱ፡ በየአምላኩ፡ ስም፡ ይሄዳል፥ እኛም፡ በአምላካችን፡ በእግዚአብሔር፡ ስም፡ ለዘላለም፡ እንሄዳለን።

፮ በዚያ፡ ቀን፡ አንካሳይቱን፡ እሰበስባለሁ፥ ይላል፡ እግዚአብሔር፥ የባከነችውንና፡ ያስጨነቅኋትንም፡ አከማቻለሁ፤ ፯ አንካሳይቱንም፡ ለቅሬታ፥ ወደ፡ ሩቅም፡ የተጣለችውን፡ ለብርቱ፡ ሕዝብ፡ አደርጋታለሁ፤ ከዚያም፡ ወዲያ፡ እስከ፡ ዘላለም፡ ድረስ፡ እግዚአብሔር፡ በጽዮን፡ ተራራ፡ በእነርሱ፡ ላይ፡ ይነግሣል። ፰ አንተም፡ የመንጋ፡ ግንብ፡ ሆይ፥ የጽዮን፡ ሴት፡ ልጅ፡ አምባ፥ ወደ፡ አንተ፡ ትመጣለች፤ የቀደመችው፡ ግዛት፥ የኢየሩሳሌም፡ ሴት፡ ልጅ፡ መንግሥት፡ ትደርሳለች።

፱ አሁንስ፡ ለምን፡ ትጮኺአለሽ? እንደምትወልድ፡ ሴት፡ ምጥ፡ የደረሰብሽ፥ ንጉሥ፡ ስለሌለሽ፡ ነውን? ወይስ፡ መካሪ፡ ስለ፡ ጠፋብሽ፡ ነውን? ፲ የጽዮን፡ ልጅ፡ ሆይ፥ እንደምትወልድ፡ ሴት፡ አምጠሽ፡ ውለጂ፤ አሁን፡ ከከተማ፡ ትወጫለሽና፥ በሜዳም፡ ትቀመጫለሽ፥ ወደ፡ ባቢሎንም፡ ትደርሻለሽ፤ በዚያም፡ ያድንሻል፥ በዚያም፡ እግዚአብሔር፡ ከጠላቶችሽ፡ እጅ፡ ይቤዥሻል።

፲፩ አሁንም፡— ርኩስ፡ ትሁን፥ ዓይናችንም፡ በጽዮን፡ ላይ፡ ይይ፡ የሚሉ፡ ብዙ፡ አሕዛብ፡ በአንቺ፡ ላይ፡ ተሰብስበዋል። ፲፪ ነገር፡ ግን፡ የእግዚአብሔርን፡ አሳብ፡ አያውቁም፥ ምክሩንም፡ አያስተውሉም፤ እንደ፡ ነዶ፡ ወደ፡ አውድማ፡ አከማችቶአቸዋልና። ፲፫ የጽዮን፡ ልጅ፡ ሆይ፥ ቀንድሽን፡ ብረት፥ ጥፍርሽንም፡ ናስ፡ አደርጋለሁና፡ ተነሺ፡ አሂጂ፤ ብዙ፡ አሕዛብንም፡ ታደቅቂአለሽ፤ ትርፋቸውንም፡ ለእግዚአብሔር፥ ሀብታቸውንም፡ ለምድር፡ ሁሉ፡ ጌታ፡ ትቀድሻለሽ።

## ምዕራፍ፡ ፭።

፩ የጭፍሮች፡ ሴት፡ ልጅ፡ ሆይ፥ ጭፍሮችሽን፡ አሁን፡ ሰብስቢ፤ ከብበ፡ አስጨንቆናል፤ የእስራኤልን፡ ፈራጅ፡ ጕንጩን፡ በበትር፡ ይመታሉ።

፪ አንቺም፡ ቤተ፡ ልሔም፡ ኤፍራታ፡ ሆይ፥ አንቺ፡ በይሁዳ፡ አእላፋት፡ መካከል፡ ትሆኚ፡ ዘንድ፡ ታናሽ፡ ነሽ፤ ከአንቺ፡ ግን፡ አወጣጡ፡ ከቀድሞ፡ ጀምሮ፡ ከዘላለም፡ የሆነ፥ በእስራኤልም፡ ላይ፡ ገዥ፡ የሚሆን፡ ይወጣልኛል። ፫ ስለዚህ፡ ወላጂቱ፡ እስክምትወልድበት፡ ጊዜ፡ ድረስ፡ አሳልፎ፡ ይሰጣቸዋል፤ የቀሩትም፡ ወንድሞቹ፡ ወደ፡ እስራኤል፡ ልጆች፡ ይመለሳሉ። ፬ እርሱም፡ ይቆማል፥ በእግዚአብሔርም፡ ኃይል፡ በአምላኩ፡ በእግዚአብሔር፡ ስም፡ ግርማ፡ መንጋውን፡ ይጠብቃል፤ እነርሱም፡ ይኖራሉ፤ እርሱ፡ አሁን፡ እስከ፡ ምድር፡ ዳርቻ፡ ድረስ፡ ታላቅ፡ ይሆናልና። ፭ ይህም፡ ለሰላም፡ ይሆናል፤ አሦራዊውም፡ ወደ፡ አገራችን፡ በገባ፡ ጊዜ፥ ምድራችንንም፡ በረገጠ፡ ጊዜ፡ ሰባት፡ እረኞችና፡ ስምንት፡ አለቆች፡ እናስነሣበታለን። ፮ የአሦርንም፡ አገር፡ በሰይፍ፥ የናምሩድንም፡ አገር፡ በመግቢያው፡ ውስጥ፡ ያፈርሳሉ፤ አሦራዊውም፡ ወደ፡ አገራችን፡ በገባ፡ ጊዜ፥ ዳርቻቻችንንም፡ በረገጠ፡ ጊዜ፡ እርሱ፡ ይታደገናል። ፯ የያዕቆብም፡ ቅሬታ፡ በብዙ፡ አሕዛብ፡ መካከል፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ እንደሚወርድ፡ ጠል፥ በሣር፡ ላይ፡ እንደሚወርድ፡ ካፊያ፤ ሰውንም፡ እንደማይጠብቅ፥ የሰውንም፡ ልጆች፡ ተስፋ፡ እንደማያደርግ፡ ይሆናል። ፰ በዱር፡ አራዊትም፡ መካከል፡ እንዳለ፡ አንበሳ፥ በበጎች፡ መንጋም፡ መካከል፡ አልፎ፡ እንደሚረግጥ፥ የሚታደግም፡ ሳይኖር፡

እንደሚነጥቅ ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ደቦል ፥ እን
ዲሁ ፡ የያዕቆብ ፡ ቅሬታ ፡ በአሕዛብና ፡ በብዙ ፡
፱ ወገኖች ፡ መካከል ፡ ይሆናል ። እጅህ ፡ በጠላ
ቶችህ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ትበል ፥ ጠላቶችህም ፡
ሁሉ ፡ ይጥፉ ።
፲ በዚያም ፡ ቀን ፡ ፈረሶችህን ፡ ከመካከልህ ፡
አጠፋለሁ ፥ ሰረገሎችህንም ፡ እሰብራለሁ ፥
፲፩ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። የምድርህንም ፡ ከተ
ሞች ፡ አጠፋለሁ ፥ ምሽጎችህንም ፡ ሁሉ ፡ አፈ
፲፪ ርሳለሁ ። መተትንም ፡ ከእጅህ ፡ አጠፋለሁ ፥
ምዋርተኞችም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አይሆኑ
፲፫ ልህም ። የተቀረጹትን ፡ ምስሎችህንና ፡ ሐውል
ቶችህን ፡ ከመካከልህ ፡ አጠፋለሁ ፥ ለእጅህም ፡
ሥራ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አትሰግድም ።
፲፬ የማምለኪያ ፡ ዐፀዶችህንም ፡ ከመካከልህ ፡ እነ
፲፭ ቅላለሁ ፥ ከተሞችህንም ፡ አፈርሳለሁ ። በልሰ
ሙም ፡ አሕዛብ ፡ ላይ ፡ በቍጣና ፡ በመዓት ፡
እበቀላለሁ ።

ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ አሁን ፡— ተነሣ ፥ በተራሮችም ፡ ፊት ፡ ተፋ
ረድ ፥ ኮረብቶችም ፡ ቃልህን ፡ ይስሙ ፡ ብሎ ፡
፪ እግዚአብሔር ፡ የሚለውን ፡ ስሙ ። ተራሮች ፡
ሆይ ፥ ጠንካሮች ፡ የምድር ፡ መሠረቶችም ፡
ሆይ ፥ እግዚአብሔር ፡ ከሕዝቡ ፡ ጋር ፡ ክርክር ፡
አለውና ፥ ከእስራኤልም ፡ ጋር ፡ ይፋረዳልና ፡
፫ የእግዚአብሔርን ፡ ክርክር ፡ ስሙ ። ሕዝቤ ፡
ሆይ ፥ ምን ፡ አድርጌሃለሁ ? በምንስ ፡ አድክሜሃ
፬ ለሁ ? መስክርብኝ ። ከግብጽ ፡ ምድር ፡ አውጥቼ
ሃለሁ ፥ ከባርነት ፡ ቤትም ፡ ተቤዥቼሃለሁ ፤ በፊ
ትህም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ ማርያምንም ፡ ልኬ
፭ ልህ ፡ ነበር ። ሕዝቤ ፡ ሆይ ፥ የሞዓብ ፡ ንጉሥ ፡
ባላቅ ፡ የመከረውን ፥ የቢዖርም ፡ ልጅ ፡ በለዓም ፡
የመለሰለትን ፡ አሁን ፡ አስብ ፤ የእግዚአብሔር
ንም ፡ የጽድቅ ፡ ሥራ ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ ከሰ
ጢም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ጌልገላ ፡ ድረስ ፡ አስብ ።
፮ ምን ፡ ይዤ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ልምጣና ፡ በልዑል ፡ አምላክ ፡ ፊት ፡ ልስገድ ?
የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የአንዱን ፡
፯ ዓመት ፡ ጥጃ ፡ ይዤ ፡ በፊቱ ፡ ልምጣን ? እግዚ
አብሔርስ ፡ በሺህ ፡ አውራ ፡ በጎች ፡ ወይስ ፡ በእ
ልፍ ፡ የዘይት ፡ ፈሳሾች ፡ ደስ ፡ ይለዋልን ?
ወይስ ፡ የበኵር ፡ ልጄን ፡ ስለ ፡ በደሌ ፥ የሆዴ
ንም ፡ ፍሬ ፡ ስለ ፡ ነፍሴ ፡ ኃጢአት ፡ እሰጣለሁን ?
፰ ሰው ፡ ሆይ ፥ መልካሙን ፡ ነግሮሃል ፤ እግዚአብ
ሔርም ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ የሚሻው ፡ ምንድር ፡
ነው ? ፍርድን ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፥ ምሕረትንም ፡
ትወድድ ፡ ዘንድ ፥ ከአምላክህም ፡ ጋር ፡ በትሕ
ትና ፡ ትሄድ ፡ ዘንድ ፡ አይደለምን ?
፱ የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ ከተማይቱን ፡ ይጠ
ራታል ፤ ስምህን ፡ መፍራት ፡ ጥበብ ፡ ነው ፤ የመ
ቅሠፍትን ፡ በትር ፥ እርሱንም ፡ ያዘጋጀ ፡ ማን ፡
፲ እንደ ፡ ሆነ ፡ ስሙ ። በውኑ ፡ በኃጢአተኛ ፡
ቤት ፡ የኃጢአት ፡ መዝገብ ፥ የተጸየፈም ፡
ውሸተኛ ፡ መስፈሪያ ፡ ገና ፡ አለ ፡ ይሆን ? በአ
፲፩ ባይ ፡ ሚዛንና ፡ በከረጢት ፡ ባለ ፡ በተንኰል ፡
መመዘኛ ፡ ንጹሕ ፡ እሆናለሁን ? ባለ ፡ ጠጎችዋን ፡
፲፪ ግፍ ፡ ሞልቶባቸዋል ፤ በእርስዋም ፡ የሚኖሩ ፡
በሐሰት ፡ ተናግረዋል ፥ ምላሳቸውም ፡ በአፋ
ቸው ፡ ውስጥ ፡ ተንኰለኛ ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ እኔ ፡
፲፫ ደግሞ ፡ በክፉ ፡ ቍስል ፡ መታሁህ ፤ ስለ ፡ ኃጢ
አትህም ፡ አፈረስሁህ ። ትበላለህ ፥ ነገር ፡ ግን ፡
፲፬ አትጠግብም ፥ ችጋርህም ፡ በመካከልህ ፡ ይሆ
ናል ፤ ትወስዳለህ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አታድንም ፤
የምታድነውንም ፡ ለሰይፍ ፡ እሰጣለሁ ። ትዘራ
፲፭ ለህ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አታጭድም ፤ ወይራውንም ፡
ትጨምቃለህ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ዘይቱን ፡ አትቀ
ባም ፤ ወይኑንም ፡ ትጨምቃለህ ፥ ነገር ፡ ግን ፡
የወይን ፡ ጠጁን ፡ አትጠጣም ። አንተን ፡ ለጥ
፲፮ ፋት ፥ በእርስዋም ፡ የሚኖሩትን ፡ ለማፍዋጫ ፡
እሰጥ ፡ ዘንድ ፡ የዘንበሪን ፡ ሥርዓትና ፡ የአክዓ
ብን ፡ ቤት ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ጠብቃችኋል ፥ በም
ክራቸውም ፡ ሄዳችኋል ፤ የሕዝቤንም ፡ ስድብ ፡
ትሸከማላችሁ ።

ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ የዛፍ ፡ ፍሬና ፡ የወይን ፡ ፍሬ ፡ ከተለቀሙ ፡
በኋላ ፡ እንደ ፡ ቀረው ፡ ቃርሚያ ፡ ሆኛለሁና ፡
ወዮልኝ ! መብል ፡ የሚሆን ፡ ዘለላ ፥ ነፍሴም ፡
የተመኘችው ፡ በመጀመሪያ ፡ የበሰለው ፡ በለስ ፡
፪ የለም ። ደግ ፡ ሰው ፡ ከምድር ፡ ጠፍቶአል ፥
በሰውም ፡ መካከል ፡ ቅን ፡ የለም ፤ ሁሉ ፡ ደምን ፡
ለማፍሰስ ፡ ያደባሉ ፥ ሰውም ፡ ሁሉ ፡ ወንድ
ሙን ፡ በመረብ ፡ ለመያዝ ፡ ይከታተለዋል ።
፫ እጆቻቸውን ፡ ለክፋት ፡ ያነሣሉ ፤ አለቃውና ፡
ፈራጁ ፡ ጉቦን ፡ ይፈልጋሉ ፥ ትልቁም ፡ ሰው ፡
እንደ ፡ ነፍሱ ፡ ምኞት ፡ ይናገራል ፤ እንዲሁም ፡
፬ ክፋትን ፡ ይጐነጕናሉ ። ከእነርሱም ፡ ሁሉ ፡
የተሻለው ፡ እርሱ ፡ እንደ ፡ አሜከላ ፡ ነው ፥
ከሁሉም ፡ ቅን ፡ የሆነው ፡ እንደ ፡ ኵርንችት ፡
ነው ፤ ጠባቆችህ ፡ የሚጐበኙበት ፡ ቀን ፡ መጥ
፭ ቶአል ፤ አሁን ፡ ይሸበራሉ ። ባልንጀራን ፡ አት
መኑ ፥ በወዳጅም ፡ አትታመኑ ፤ የአፍህን ፡
ደጅ ፡ በብብትህ ፡ ከምትተኛው ፡ ጠብቅ ።
፮ ወንድ ፡ ልጅ ፡ አባቱን ፡ ይንቃልና ፥ ሴት ፡
ልጅ ፡ በእናትዋ ፡ ላይ ፥ ምራቲቱም ፡ በአማ
ትዋ ፡ ላይ ፡ ትነሣለችና ፥ የሰው ፡ ጠላቶች ፡
የቤቱ ፡ ሰዎች ፡ ናቸውና ።
፯ እኔ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እመለከታ
ለሁ ፥ የመድኃኒቴንም ፡ አምላክ ፡ ተስፋ ፡ አደ
፰ ርጋለሁ ፤ አምላኬም ፡ ይሰማኛል ። ጠላቴ ፡
ሆይ ፥ ብወድቅ ፡ እነሣለሁና ፥ በጨለማም ፡ ብቀ
መጥ ፡ እግዚአብሔር ፡ ብርሃን ፡ ይሆንልኛልና ፡
፱ በእኔ ፡ ላይ ፡ ደስ ፡ አይበልሽ ። በእግዚአብሔር ፡
ላይ ፡ ኃጢአት ፡ ሠርቻለሁና ፡ እስኪምዋገትልኝ ፡
ድረስ ፥ ፍርድን ፡ ለእኔ ፡ እስኪያደርግ ፡ ድረስ ፡
ቍጣውን ፡ እታገሣለሁ ። ወደ ፡ ብርሃን ፡ ያወ
፲ ጣኛል ፥ ጽድቅንም ፡ አያለሁ ። ጠላቴም ፡ ታያ

ለች ፥ እኔንም ፡— አምላክህ ፡ እግዚአብሔር ፡
ወዴት ፡ ነው ? ያለች ፡ በእፍረት ፡ ትከደናለች ።
፲፩፤ ዓይኖቼ ፡ ይመለከቱአታል ፤ አሁን ፡ እንደ ፡ መን
ገድ ፡ ጭቃ ፡ ትረገጣለች ። ቅጥርሽ ፡ በሚሠራ
በት ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ድንበርሽ ፡ ትስፋፋለች ።
፲፪፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ ከአሦርና ፡ ከግብጽ ፡ ከተሞች ፥ ከግ
ብጽ ፡ እስከ ፡ ወንዙ ፥ ከባሕርም ፡ እስከ ፡ ባሕር ፥
ከተራራም ፡ እስከ ፡ ተራራ ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡
፲፫፤ ይመጣሉ ። ምድሪቱ ፡ ግን ፡ በሚኖሩባት ፡ በሥ
ራቸው ፡ ፍሬ ፡ ምክንያት ፡ በድማ ፡ ትሆናለች ።
፲፬፤ በቀርሜሎስ ፡ መካከል ፡ በለው ፡ ዱር ፡ ብቻ
ቸውን ፡ የተቀመጡት ፡ ሰዎችህ ፥ የርስትህን ፡
በጎች ፥ በበትርህ ፡ አግድ ፤ እንደ ፡ ቀደመውም ፡
፲፭፤ ዘመን ፡ በባሳንና ፡ በገለዓድ ፡ ይሰማሩ ። ከግ
ብጽ ፡ ምድር ፡ እንደ ፡ ወጣህበት ፡ ዘመን ፡ ተአ
፲፮፤ ምራትን ፡ አሳያቸዋለሁ ። አሕዛብ ፡ አይተው ፡
በኃይለታቸው ፡ ሁሉ ፡ ያፍራሉ ፤ እጃቸውን ፡
በአፋቸው ፡ ላይ ፡ ያኖራሉ ፥ ጆሮአቸውም ፡
ትደነቍራለች ፤ እንደ ፡ እባብም ፡ መሬት ፡ ይል ፲፯፤
ሳሉ ፥ እንደ ፡ ምድርም ፡ ተንቀሳቃሾች ፡ እየ
ተንቀጠቀጡ ፡ ከግንባቸው ፡ ይመጣሉ ፤ ፈርተ
ውም ፡ ወደ ፡ አምላካችን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ይመጣሉ ፥ ስለ ፡ አንተም ፡ ይፈራሉ ።
በደልን ፡ ይቅር ፡ የሚል ፥ የርስቱንም ፡ ቅሬታ ፡ ፲፰፤
ዓመፅ ፡ የሚያሳልፍ ፡ እንደ ፡ አንተ ፡ ያለ ፡ አም
ላክ ፡ ማን ፡ ነው ? ምሕረትን ፡ ይወድዳልና ፡
ቍጣውን ፡ ለዘላለም ፡ አይጠብቅም ። ተመልሶ ፡ ፲፱፤
ይምረናል ፤ ክፋታችንንም ፡ ይጠቀጥቃል ፥
ኃጢአታችንንም ፡ በባሕሩ ፡ ጥልቅ ፡ ይጥለ
ዋል ። ከቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ጀምረህ ፡ ለአባቶቻ ፳፤
ችን ፡ የማልህላቸውን ፡ እውነት ፡ ለያዕቆብ ፥
ምሕረትንም ፡ ለአብርሃም ፡ ታደርጋለህ ።

# ትንቢተ ፡ ኢዮኤል ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ ወደ ፡ ባቱኤል ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢዮኤል ፡ የመ
ጣው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ።
፪፤ እናንተ ፡ ሽማግሌዎች ፥ ይህን ፡ ስሙ ፤ በምድ
ርም ፡ የምትኖሩ ፡ ሁሉ ፥ አድምጡ ። ይህ ፡ በዘ
መናችሁ ፡ ወይስ ፡ በአባቶቻችሁ ፡ ዘመን ፡ ሆኖ ፡
፫፤ ነበርን ? ይህን ፡ ለልጆቻችሁ ፡ ንገሩ ፤ ልጆቻች
ሁም ፡ ለልጆቻቸው ፥ ልጆቻቸውም ፡ ለኋለ
፬፤ ኛው ፡ ትውልድ ፡ ይንገሩ ። ከተምች ፡ የቀረ
ውን ፡ አንበጣ ፡ በላው ፤ ከአንበጣም ፡ የቀረ
ውን ፡ ደጎብያ ፡ በላው ፤ ከደጎብያም ፡ የቀረውን ፡
ኩብኩባ ፡ በላው ።
፭፤ በተሃ ፡ ወይን ፡ ጠጃችሁ ፡ ከአፋችሁ ፡ ተወ
ግዶአልና ፡ እናንተ ፡ ሰካራሞች ፥ ነቅታችሁ ፡
አልቅሱ ፤ እናንተም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ የምት
፮፤ ጠጡ ፡ ሁሉ ፥ ዋይ ፡ በሉ ። ቍጥርም ፡ የሌለው ፡
ብርቱ ፡ ሕዝብ ፡ በምድሬ ፡ ላይ ፡ ወጥቶአልና ፤
ጥርሳቸው ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ጥርስ ፥ መንጋጋ
ቸውም ፡ እንደ ፡ እንስቲቱ ፡ አንበሳ ፡ መንጋጋ ፡
፯፤ ነው ። ወይኔን ፡ ባዶ ፡ ምድር ፡ አደረገው ፥ በለ
ሴንም ፡ ሰበረው ፤ ባዶም ፡ አደረገው ፥ ጣለውም ፤
ቅርንጫፎቹም ፡ ነጡ ።
፰፤ ለቍንጅናዋ ፡ ባል ፡ ማቅ ፡ ለብሳ ፡ እንደምታ
፱፤ ለቅስ ፡ ድንግል ፡ አልቅሺ ። የእህሉ ፡ ቍርባ
ንና ፡ የመጠጡ ፡ ቍርባን ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ ተወግዶአል ፤ የእግዚአብሔርም ፡ አገል
፲፤ ጋዮች ፡ ካህናቱ ፡ አለቀሱ ። እህሉ ፡ ጠፍቶአ
ልና ፥ ወይኑም ፡ ደርቆአልና ፥ ዘይቱም ፡ ጎድ
ሎአልና ፡ እርሻው ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሆኖአል ፥
፲፩፤ ምድሪቱም ፡ አልቅሳለች ። መከሩ ፡ ከእርሻቸው ፡
ጠፍቶአልና ፡ ገበሬዎች ፡ ስለ ፡ ስንዴውና ፡ ስለ ፡
ገብሱ ፡ አፈሩ ፤ የወይን ፡ አትክልተኞችም ፡
አለቀሱ ። ወይኑ ፡ ደርቆአል ፥ በለሱም ፡ ጠው ፲፪፤
ልጎአል ፤ ሮማኑና ፡ ተምሩ ፡ እንኮዩም ፡ የምድ
ርም ፡ ዛፎች ፡ ሁሉ ፡ ደርቀዋል ፤ ደስታም ፡
ከሰው ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ ርቆአል ።
የእህሉ ፡ ቍርባንና ፡ የመጠጡ ፡ ቍርባን ፡ ፲፫፤
ከአምላካችሁ ፡ ቤት ፡ ቀርቶአልና ፡ እናንተ ፡ ካህ
ናት ፥ ማቅ ፡ ታጥቃችሁ ፡ አልቅሱ ፤ እናንተም ፡
የመሠዊያ ፡ አገልጋዮች ፥ ዋይ ፡ በሉ ፤ እናንተ ፡
የአምላኬ ፡ አገልጋዮች ፥ ኑ ፥ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡
በማቅ ፡ ላይ ፡ ተኙ ። ጾምን ፡ ቀድሱ ፥ ጉባኤው ፲፬፤
ንም ፡ አውጁ ፤ ሽማግሌዎችንና ፡ በምድር ፡ የሚ
ኖሩትን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ አምላካችሁ ፡ ወደ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ሰብስቡ ፥ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔርም ፡ ጩኹ ።
የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ቀርቦአልና ፡ ለቀኑ ፡ ፲፭፤
ወዮ ! እርሱም ፡ ሁሉን ፡ ከሚችል ፡ ከአምላክ ፡
ዘንድ ፡ እንደ ፡ ጥፋት ፡ ይመጣል ። ከዓይናችን ፡ ፲፮፤
ፊት ፡ምግብ ፥ ከአምላካችንም ፡ ቤት ፡ ደስታና ፡
እልልታ ፡ የጠፋ ፡ አይደለምን ? ዘሩ ፡ በምድር ፡ ፲፯፤
ውስጥ ፡ በሰበሰ ፤ እህሉ ፡ ደርቆአልና ፡ ጎተራ
ዎቹ ፡ ባዶ ፡ ናቸው ፥ ጎታዎቹም ፡ ፈርሰዋል ።
እንስሶች ፡ እጅግ ፡ ጮኹ ፤ የላምም ፡ መንጎች ፡ ፲፰፤
ማሰማርያ ፡ የላቸውምና ፡ ተጠራጠሩ ፤ የበግም ፡
መንጎች ፡ ጠፍተዋል ። አቤቱ ፥ እሳት ፡ የም ፲፱፤
ድረ ፡ በዳውን ፡ ማሰማርያ ፡ በልቶአልና ፥ ነበ
ልባሉም ፡ የዱሩን ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ አቃጥሎአ
ልና ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እጮኻለሁ ። ፈሳሹ ፡ ውኃ ፡ ፳፤
ደርቆአልና ፥ እሳቱም ፡ የምድረ ፡ በዳውን ፡
ማሰማርያ ፡ በልቶአልና ፡ የምድር ፡ አራዊት ፡
ወደ ፡ አንተ ፡ አለኸለኹ ።

## ምዕራፍ፡፪።

፩፡ የእግዚአብሔር፡ቀን፡መጥቶአልና÷እርሱም፡ቀርቦአልና፡በጽዮን፡መለከትን፡ንፉ÷በቅዱሱም፡ተራራዬ፡ላይ፡እሪ፡በሉ፤በምድርም፡የሚኖሩ፡ሁሉ፡ይንቀጥቀጡ፤ ፪፡ የእግዚአብሔር፡ቀን፡መጥቶአልና፤የጨለማና፡የጭጋግ፡ቀን÷የደመናና፡የድቅድቅ፡ጨለማ፡ቀን፡ነው፤ታላቅና፡ብርቱ፡ሕዝብ፡በተራሮች፡ላይ፡እንደ፡ወገግታ፡ተዘርግቶአል፤ከዘላለምም፡ጀምሮ፡እንደ፡እነርሱ፡ያለ፡አልነበረም÷ከእነርሱም፡በኋላ፡እስከ፡ብዙ፡ትውልድ፡ድረስ፡እንደ፡እነርሱ፡ያለ፡ከእንግዲህ፡ወዲህ፡አይሆንም። ፫፡ እሳት፡በፊታቸው፡ትበላለች÷በኋላቸውም፡ነበልባል፡ታቃጥላለች፤ምድሪቱ፡በፊታቸው፡እንደ፡ዔድን፡ገነት÷በኋላቸውም፡የምድረ፡በዳ፡በረሃ፡ናት፤ከእነርሱም፡የሚያመልጥ፡የለም።

፬፡ መልካቸው፡እንደ፡ፈረስ፡መልክ፡ነው÷ ፭፡ እንደ፡ፈረሰኞችም፡ይሮጣሉ። በተራራ፡ላይ፡እንዳሉ፡ሰረገሎች፡ድምፅ÷ገለባውንም፡እንደሚበላ፡እንደ፡እሳት፡ነበልባል፡ድምፅ÷ለሰልፍም፡እንደ፡ተዘጋጀ፡እንደ፡ብርቱ፡ሕዝብ፡ያኰበኵባሉ። ፮፡ ከፊታቸው፡አሕዛብ፡ይንቀጠቀጣሉ፤የሰውም፡ፊት፡ሁሉ፡ይጠቍራል። ፯፡ እንደ፡ኃያላን፡ይሮጣሉ÷እንደ፡ሰልፈኞችም፡በቅጥሩ፡ላይ፡ይወጣሉ፤እያንዳንዱም፡በመንገዱ፡ላይ፡ይራመዳል÷ከእርምጃቸውም፡አያፈገፍጉም። ፰፡ አንዱ፡ከንዱ፡ጋር፡አይጋፋም÷እያንዳንዱም፡መንገዱን፡ይጠበጥባል፤በሰልፉ፡መካከል፡ያልፋሉ÷እነርሱም፡አይቈስሉም። ፱፡ በከተማም፡ያኰበኵባሉ÷በቅጥሩም፡ላይ፡ይሮጣሉ፤ወደ፡ቤቶችም፡ይወጣሉ÷እንደ፡ሌባም፡በመስኮቶች፡ይገባሉ። ፲፡ ምድሪቱም፡ከፊታቸው፡ትናወጣለች÷ሰማያትም፡ይንቀጠቀጣሉ፤ፀሐይና፡ጨረቃም፡ይጨልማሉ÷ከዋክብትም፡ብርሃናቸውን፡ይሰውራሉ። ፲፩፡ እግዚአብሔርም፡በሠራዊቱ፡ፊት፡ድምፁን፡ይሰጣል፤ሰፈሩ፡እጅግ፡ብዙ፡ነውና÷ቃሉንም፡የሚያደርግ፡እርሱ፡ኃያል፡ነውና፤የእግዚአብሔርም፡ቀን፡ታላቅና፡እጅግ፡የሚያስፈራ፡ነውና፡ማንስ፡ይችለዋል?

፲፪፡ አሁንስ÷ይላል፡እግዚአብሔር÷በፍጹም፡ልባችሁ÷በጾምም÷በልቅሶ፡በዋይታ፡ ፲፫፡ ወደ፡እኔ፡ተመለሱ። ልባችሁን፡እንጂ፡ልብሳችሁን፡አትቅደዱ፤አምላካችሁም፡እግዚአብሔር፡ቸርና፡መሐሪ÷ቍጣው፡የዘገየ÷ምሕረቱም፡የበዛ÷ለክፋትም፡የተጸጸተ፡ነውና፡ወደ፡እርሱ፡ተመለሱ። ፲፬፡ የሚመለስና፡የሚጸጸት፡እንደ፡ሆነ÷ለአምላካችሁም፡ለእግዚአብሔር፡የእህልና፡የመጠጥ፡ቍርባን፡የሚሆነውን፡በረከት፡የሚያተርፍ፡እንደ፡ሆነ፡ማን፡ያውቃል?

፲፭፡ በጽዮን፡መለከትን፡ንፉ÷ጾምንም፡ቀድሱ÷ ፲፮፡ ጉባኤውንም፡አውጁ÷ሕዝቡንም፡አከማቹ÷ማኅበሩንም፡ቀድሱ÷ሽማግሌዎቹንም፡ሰብስቡ÷ሕፃናቱንና፡ጡት፡የሚጠቡትን፡አከማቹ፤ሙሽራው፡ከእልፍኙ÷ሙሽራይቱም፡ከጫጉላዋ፡ይውጡ። ፲፯፡ የእግዚአብሔርም፡አገልጋዮች፡ካህናት፡ከወለሉና፡ከመሠዊያው፡መካከል፡እያለቀሱ፦አቤቱ÷ለሕዝብህ፡ራራ÷አሕዛብም፡እንዳይነቅፉአቸው፡ርስትህን፡ለማላገጫ፡አሳልፈህ፡አትስጥ፤ከአሕዛብ፡መካከል፦አምላካቸው፡ወዴት፡ነው?ስለ፡ምን፡ይላሉ?ይበሉ።

፲፰፡ እግዚአብሔርም፡ስለ፡ምድሩ፡ቀና÷ለሕዝቡም፡ራራለት። ፲፱፡ እግዚአብሔርም፡መልሶ፡ሕዝቡን፦እነሆ÷እህልንና፡ወይንን፡ዘይትንም፡እሰድድላችኋለሁ÷እናንተም፡በእርሱ፡ትጠግባላችሁ፤ከእንግዲህም፡ወዲያ፡በአሕዛብ፡መካከል፡መሰደቢያ፡አላደርጋችሁም። ፳፡ የሰሜንንም፡ሠራዊት፡ከእናንተ፡ዘንድ፡አርቃለሁ÷ወደ፡በረሃና፡ወደ፡ምድረ፡በዳ÷ፊቱን፡ወደ፡ምሥራቁ፡ባሕር÷ጀርባውንም፡ወደ፡ምዕራቡ፡ባሕር፡አድርጌ፡አሳድደዋለሁ፤እርሱም፡ትዕቢትን፡አድርጎአልና፡ግማቱ፡ይወጣል÷ክርፋቱም፡ይነሣል፡አለ።

፳፩፡ ምድር፡ሆይ÷እግዚአብሔር፡ታላቅ፡ነገር፡አድርጎአልና፡አትፍሪ÷ደስም፡ይበልሽ÷ ፳፪፡ እልልም፡በዪ። እናንተ፡የምድር፡እንስሶች፡ሆይ÷የምድረ፡በዳው፡ማሰማርያ፡ለምልሞአልና÷ዛፉም፡ፍሬውን፡አፍርቶአልና÷በለሱና፡ወይኑም፡ኃይላቸውን፡ሰጥተዋልና፡አትፍሩ። ፳፫፡ እናንተ፡የጽዮን፡ልጆች÷አምላካችሁ፡እግዚአብሔር፡የፊተኛውን፡ዝናብ፡በጽድቅ፡ሰጥቶአችኋልና÷እንደ፡ቀድሞውም፡የፊተኛውንና፡የኋለኛውን፡ዝናብ፡አዝንቦላችኋልና፡በእርሱ፡ደስ፡ይበላችሁ÷ለእርሱም፡እልል፡በሉ። ፳፬፡ አውድማዎችም፡እህልን፡ይሞላሉ÷መጥመቂያዎችም፡የወይን፡ጠጅንና፡ዘይትን፡አትረፍርፈው፡ያፈስሳሉ። ፳፭፡ የሰደድሁባችሁ፡ታላቁ፡ሠራዊቴ፡አንበጣና፡ደጎብያ፡ኩብኩባና፡ተምች፡የበላቸውን፡ዓመታት፡እመልስላችኋለሁ። ፳፮፡ ብዙ፡መብል፡ትበላላችሁ÷ትጠግቡማላችሁ፤ከእናንተም፡ጋር፡ተአምራትን፡የሠራውን፡የአምላካችሁን፡የእግዚአብሔርን፡ስም፡ታመሰግናላችሁ፤ሕዝቤም፡ለዘላለም፡አያፍርም። ፳፯፡ እኔም፡በእስራኤል፡መካከል፡እንዳለሁ÷እኔም፡አምላካችሁ፡እግዚአብሔር፡እንደ፡ሆንሁ÷ከእኔም፡በቀር፡ሌላ፡አምላክ፡እንደሌለ፡ታውቃላችሁ፤ሕዝቤም፡ለዘላለም፡አያፍርም።

፳፰፡ ከዚህም፡በኋላ፡እንዲህ፡ይሆናል፤መንፈሴን፡በሥጋ፡ለባሽ፡ሁሉ፡ላይ፡አፈስሳለሁ፤ወንዶችና፡ሴቶች፡ልጆቻችሁም፡ትንቢት፡ይናገራሉ÷ሽማግሌዎቻችሁም፡ሕልምን፡ያልማሉ÷ጕበዞቻችሁም፡ራእይ፡ያያሉ፤

፳፱፤ ደግሞም ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ በወንዶችና ፡ በሴ
ቶች ፡ ባሪያዎች ፡ ላይ ፡ መንፈሴን ፡ አፈስሳለሁ ።
፴፤ በላይ ፡ በሰማይ ፡ ድንቆችን ፡ አሳያለሁ ÷ በታች ፡
በምድርም ፡ ደምና ፡ እሳት ፡ የጢስም ፡ ጭጋግ ።
፴፩፤ ታላቁና ፡ የሚያስፈራው ፡ የእግዚአብሔር ፡
ቀን ፡ ሳይመጣ ፡ ፀሐይ ፡ ወደ ፡ ጨለማ ÷ ጨረ
፴፪፤ ቃም ፡ ወደ ፡ ደም ፡ ይለወጣል ። እንዲህም ፡
ይሆናል ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ የሚጠራ ፡
ሁሉ ፡ ይድናል ፤ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተና
ገረ ÷ በጽዮን ፡ ተራራና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ መድ
ኃኒት ፡ ይገኛል ። ደግሞም ፡ እግዚአብሔር ፡
የጠራቸው ÷ የምስራች ፡ የሚሰበከላቸው ፡ ይገ
ኛሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፤ እነሆም ÷ በዚያ ፡ ወራትና ፡ በዚያ ፡ ዘመን ÷
የይሁዳንና ፡ የኢየሩሳሌምን ፡ ምርከ ፡ በምመ
፪፤ ልስበት ፡ ጊዜ ÷ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ ሰብስቤ ፡
ወደ ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ ሸለቆ ፡ አወርዳቸዋለሁ ፤
በዚያም ፡ ስለ ፡ ሕዝቤና ፡ ስለ ፡ ርስቴ ፡ ስለ ፡
እስራኤል ፡ በአሕዛብ ፡ መከከል ፡ የበተኑአቸ
ውን ፡ ምድሬንም ፡ የተከፈሉአትን ፡ እፋረድባ
፫፤ ቸዋለሁ ። በሕዝቤም ፡ ላይ ፡ ዕጣ ፡ ተጣጣሉ ፤
ወንድ ፡ ልጅን ፡ ለጋለሞታ ፡ ዋጋ ፡ ሰጡ ÷ ሴት ፡
ልጅን ፡ ለወይን ፡ ጠጅ ፡ ሸጡ ÷ ጠጡም ።
፬፤ ጢሮስና ፡ ሲዶና ፡ የፍልስጥኤምም ፡ ግዛት ፡
ሁሉ ፡ ሆይ ÷ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ለእኔ ፡ ምን ፡
አለኝ ? በውኑ ፡ ብድራትን ፡ ትመልሱልኛላ
ችሁን ? ብድራትን ፡ ብትመልሱልኝ ፡ ፈጥኜ ፡
በችኰላ ፡ ብድራታችሁን ፡ በራሳችሁ ፡ ላይ ፡
፭፤ እመልሳለሁ ። ብሬንና ፡ ወርቄን ፡ ወስዳችኋ
ልና ÷ የተወደደውንም ፡ መልካሙን ፡ ዕቃዬን ፡
፮፤ ወደ ፡ መቅደሳችሁ ፡ አግብታችኋልና ÷ ከዳር
ቻቸውም ፡ ታርቁአቸው ፡ ዘንድ ፡ የይሁዳንና ፡
የኢየሩሳሌምን ፡ ልጆች ፡ ለግሪክ ፡ ሰዎች ፡ ሸጣ
፯፤ ችኋልና ÷ እነሆ ÷ እነርሱን ፡ ከሸጣችሁበት ፡
ስፍራ ፡ አስነሣቸዋለሁ ÷ ብድራታችሁንም ፡
፰፤ በራሳችሁ ፡ ላይ ፡ እመልሳለሁ ። እግዚአብሔር ፡
ተናግሮአልና ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻች
ሁን ፡ በይሁዳ ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ እሸጣለሁ ÷ እነ
ርሱም ፡ ለሩቆቹ ፡ ሕዝብ ፡ ለሳባ ፡ ሰዎች ፡ ይሸ
ጡአችኋል ።

፱፤ ይህን ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ አውጁ ፤ ለሰ
ልፍ ፡ ተዘጋጁ ፤ ኃያላንን ፡ አስነሡ ፤ ሰልፈኞች ፡
፲፤ ሁሉ ፡ ይቅረቡ ፡ ይውጡም ። ማረሻችሁን ፡
ሰይፍ ÷ ማጭዳችሁንም ፡ ጦር ፡ ለማድረግ ፡
ቀጥቅጡ ፤ ደካማውም ፡— እኔ ፡ ብርቱ ፡ ነኝ ፡
፲፩፤ ይበል ። እናንተ ፡ በዙሪያ ፡ ያላችሁ ፡ አሕዛብ ፡
ሁሉ ÷ ቸኵላችሁ ፡ ኑ ÷ ተሰብሰቡ ፤ አቤቱ ÷
፲፪፤ ኃያላኖችህን ፡ ወደዚያ ፡ አውርድ ። አሕዛብ ፡
ይነሡ ÷ ወደ ፡ ኢዮሣፍጥ ፡ ሸለቆም ፡ ይውጡ ፤
በዙሪያ ፡ ባሉ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እፈርድ ፡
፲፫፤ ዘንድ ፡ በዚያ ፡ እቀመጣለሁና ። መከሩ ፡ ደርሶ
አልና ፡ ማጭድ ፡ ስደዱ ፤ መጥመቂያውም ፡
ሞልቶአልና ፡ ኑ ፡ እርገጡ ፤ ክፋታቸውም ፡
በዝቶአልና ፡ መጥመቂያ ፡ ሁሉ ፡ ፈስሶአል ።
፲፬፤ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ በፍርድ ፡ ሸለቆ ፡ ቀር
ቦአልና ፡ የብዙ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ውካታ ፡ በፍ
፲፭፤ ርድ ፡ ሸለቆ ፡ አለ ። ፀሐይና ፡ ጨረቃ ፡ ጨል
መዋል ÷ ከዋክብትም ፡ ብርሃናቸውን ፡ ሰውረ
፲፮፤ ዋል ። እግዚአብሔርም ፡ በጽዮን ፡ ሆኖ ፡ ድም
ፁን ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡ ይጮኻል ÷ በኢየሩሳሌ
ምም ፡ ሆኖ ፡ ቃሉን ፡ ይሰጣል ፤ ሰማይና ፡ ምድ
ርም ፡ ይናወጣሉ ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ለሕ
ዝቡ ፡ መሸሸጊያ ÷ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
፲፯፤ መጠጊያ ፡ ይሆናል ። እኔም ፡ በተቀደሰው ፡
ተራራዬ ፡ በጽዮን ፡ የምቀመጥ ፡ አምላካችሁ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ፤
የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኢየሩሳሌም ፡ የተቀደሰች ፡
ትሆናለች ÷ እንግዶችም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
አያልፉባትም ።
፲፰፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ፤ ተራሮች ፡
በተሃ ፡ ጠጅ ፡ ያንጠባጥባሉ ÷ ኮረብቶችም ፡
ወተትን ፡ ያፈስሳሉ ÷ በይሁዳም ፡ ያሉት ፡ ፈፋ
ዎች ፡ ሁሉ ፡ ውኃን ፡ ያጐርፉሉ ፤ ከእግዚአብ
ሔርም ፡ ቤት ፡ ምንጭ ፡ ትፈልቃለች ÷ የሰጢ
፲፱፤ ምንም ፡ ሸለቆ ፡ ታጠጣለች ። በአገራቸው ፡ ንጹ
ሑን ፡ ደም ፡ አፍስሰዋልና ፡ በይሁዳ ፡ ልጆች ፡
ላይ ፡ ስላደረጉት ፡ ግፍ ፡ ግብጽ ፡ ምድረ ፡ በዳ ÷
፳፤ ኤዶምያስም ፡ በረሃ ፡ ይሆናል ። ነገር ፡ ግን ፡
ይሁዳ ፡ ለዘላለም ÷ ኢየሩሳሌምም ፡ ለልጅ ፡
፳፩፤ ልጅ ፡ መኖሪያ ፡ ይሆናል ። እኔም ፡ ንጹሕ ፡ ያላ
ደረግሁትን ፡ ደማቸውን ፡ ንጹሕ ፡ አደርገዋ
ለሁ ÷ እግዚአብሔርም ፡ በጽዮን ፡ ያድራል ።

# ት ን ቢ ተ ፡ አ ብ ድ ዩ ።

Selah

፩፤ የአብድዩ ፡ ራእይ ።
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ኤዶምያስ ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወሬ ፡ ሰም
ተናል ፤ መልእክተኛ ፡ ወደ ፡ አሕዛብ ፡ ተልኮ ፡—
ተነሡ ÷ በላይዋም ፡ በሰልፍ ፡ እንነሣ ፡ ብሎ
፪፤ አል ። እነሆ ÷ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ታናሽ ፡ አድ
፫፤ ርጌሃለሁ ፤ አንተ ፡ እጅግ ፡ ተንቀሃል ። በተሰነ
ጠቀ ፡ ዓለት ፡ ውስጥ ፡ የምትኖር ÷ ማደሪያህ
ንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደረግህ ÷ በልብህም ፡—
ወደ ፡ ምድር ፡ የሚያወርደኝ ፡ ማን ፡ ነው ? የም
ትል ፡ አንተ ፡ ሆይ ÷ የልብህ ፡ ትዕቢት ፡ አታል
፬፤ ሎሃል ። እንደ ፡ ንስር ፡ መጥቀህ ፡ ብትወጣ ÷

ስለዚህ ፡ ወደ ፡ ተርሴስ ፡ ለመኰብለል ፡ ፈጥኜ ፡
፫ ነበር ። አሁንም ÷ አቤቱ ÷ ከሕይወት ፡ ሞት ፡
ይሻለኛልና ፡ እባክህ ÷ ነፍሴን ፡ ከእኔ ፡ ውሰድ ፡
፬ አለው ። እግዚአብሔርም ፡— በውኑ ፡ ትቈጣ ፡
ዘንድ ፡ ይገባሃልን ? አለ ።
፭ ዮናስም ፡ ከከተማይቱ ፡ ወጣ ÷ ከከተማይ
ቱም ፡ በስተ ፡ ምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ተቀመጠ ፤ ከተ
ማይቱንም ፡ የሚያገኛትን ፡ እስኪያይ ፡ ድረስ ፡
በዚያ ፡ ለራሱ ፡ ዳስ ፡ ሠርቶ ፡ ከጥላው ፡ በታች ፡
፮ ተቀመጠ ። እግዚአብሔር ፡ አምላክም ፡ ቅል ፡
አዘጋጀ ÷ ከጭንቀቱም ፡ ታድነው ፡ ዘንድ ፡ በራሱ ፡
ላይ ፡ ጥላ ፡ እንድትሆን ፡ በዮናስ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡
ከፍ ፡ አደረጋት ፤ ዮናስም ፡ ስለ ፡ ቅሊቱ ፡ እጅግ ፡
፯ ደስ ፡ አለው ። በነጋው ፡ ግን ፡ ወገግ ፡ በለ ፡ ጊዜ ፡
እግዚአብሔር ፡ ትልን ፡ አዘጋጀ ÷ እርስዋም ፡
፰ ቅሊቱን ፡ እስክትደርቅ ፡ ድረስ ፡ መታቻት ። ፀሐ
ይም ፡ በወጣች ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትኩስ ፡
የምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ አዘጋጀ ፤ ዮናስ ፡ እስኪዝል ፡
ድረስም ፡ ፀሐይ ፡ ራሱን ፡ መታው ፤ ለራሱም ፡
ሞትን ፡ ፈለገና ፡— ከሕይወት ፡ ሞት ፡ ይሻለ
፱ ኛል ፡ አለ ። እግዚአብሔርም ፡ ዮናስን ፡—
በውኑ ፡ ስለዚች ፡ ቅል ፡ ትቈጣ ፡ ዘንድ ፡ ይገባሃ
ልን ? አለው ። እርሱም ፡— እስከ ፡ ሞት ፡ ድረስ ፡
፲ እቈጣ ፡ ዘንድ ፡ ይገባኛል ፡ አለ ። እግዚአብሔ
ርም ፡— አንተ ፡ ትበቅል ፡ ዘንድ ፡ ላልደከምህ
በት ፡ ላላሳደግሃትም ÷ በአንድ ፡ ሌሊት ፡ ለበቀ
ለች ÷ በአንድ ፡ ሌሊትም ፡ ለደረቀችው ፡ ቅል ፡
፲፩ አዝነሃል ። እኔስ ፡ ቀኛቸውንና ፡ ግራቸውን ፡
የማይለዩ ፡ ከመቶ ፡ ሀያ ፡ ሺህ ፡ የሚበልጡ ፡ ሰዎ
ችና ፡ ብዙ ፡ እንስሶች ፡ ላሉበት ፡ ለታላቂቱ ፡
ከተማ ፡ ለነነዌ ፡ አላዝንምን ? አለው ።

# ትንቢተ ፡ ናሆም ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ ስለ ፡ ነነዌ ፡ የተነገረ ፡ ሸክም ፤ የኤልቆሻዊው ፡
የናሆም ፡ የራእዩ ፡ መጽሐፍ ፡ ይህ ፡ ነው ።
፪ እግዚአብሔር ፡ ቀናተኛና ፡ ተበቃይ ፡ አም
ላክ ፡ ነው ፤ እግዚአብሔር ፡ ተበቃይና ፡ መዓትን ፡
የተሞላ ፡ ነው ፤ እግዚአብሔር ፡ ተቃዋሚዎ
ቹን ፡ ይበቀላል ÷ ለጠላቶቹም ፡ ቍጣውን ፡
፫ ይጠብቃል ። እግዚአብሔር ፡ ትዕግሥተኛ ÷
ኃይሉም ፡ ታላቅ ፡ ነው ÷ በደለኛውንም ፡—
ንጹሕ ፡ ነህ ፡ አይልም ፤ እግዚአብሔር ፡ በወጀ
ብና ፡ በዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ውስጥ ፡ መንገድ ፡ አለው ÷
፬ ደመናም ፡ የእግሩ ፡ ትቢያ ፡ ነው ። ባሕሩንም ፡
ይገሥጻታል ÷ ያደርቃትማል ÷ ወንዞችንም ፡
ሁሉ ፡ ያደርቃል ፤ ባሳንና ፡ ቀርሜሎስም ፡ ላል
ተዋል ÷ የሊባኖስም ፡ አበበ ፡ ጠውልጎአል ።
፭ ተራሮችም ፡ ከእርሱ ፡ የተነሣ ፡ ታወኩ ÷ ኮረብ
ቶችም ፡ ቀለጡ ፤ ምድርና ፡ ዓለም ፡ የሚኖሩበ
፮ ትም ፡ ሁሉ ፡ ከፊቱ ፡ ተናወጡ ። በቍጣው ፡
ፊት ፡ የሚቆም ፡ ማን ፡ ነው ? የቍጣውንም ፡
ትኵሳት ፡ ማን ፡ ይታገሣል ? መዓቱ ፡ እንደ ፡
እሳት ፡ ይፈስሳል ÷ ከእርሱም ፡ የተነሣ ፡ ዓለ
፯ ቶች ፡ ተሰነጠቁ ። እግዚአብሔር ፡ መልካም ፡
ነው ÷ በመከራ ፡ ቀንም ፡ መሸሸጊያ ፡ ነው ፤ በእ
፰ ርሱ ፡ የሚታመኑትንም ፡ ያውቃል ። ስፍራዋን ፡
ግን ፡ በሚያጥለቀልቅ ፡ ጐርፍ ፡ ፈጽሞ ፡ ያጠፋ
ታል ÷ ጠላቶቹንም ፡ ወደ ፡ ጨለማ ፡ ያሳድዳ
ቸዋል ።
፱ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ የምታስቡት ፡ ምን
ድር ፡ ነው ? እርሱ ፡ ፈጽሞ ፡ ያጠፋል ÷ መከ
፲ ራም ፡ ሁለተኛ ፡ አይነሣም ። እርስ ፡ በእርሳ
ቸው ፡ እንደ ፡ ተመሰቃቀለ ፡ እሾህ ፡ ቢሆኑ ÷
በመጠጣቸውም ፡ ቢሰክሩ ፡ እንደ ፡ ደረቅ ፡
፲፩ ገለባ ፡ ፈጽመው ፡ ይጠፋሉ ። በእግዚአብሔር ፡
ላይ ፡ በክፉ ፡ የሚያስብ ÷ ክፋትን ፡ የሚመክር ÷
፲፪ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ ወጥቶአል ። እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— ኃይለኞችና ፡ ብዙዎች ፡
ቢሆኑ ፡ እንዲሁ ፡ ይቈረጣሉ ÷ እርሱም ፡ ያል
ቃል ። እኔም ፡ አስጨንቄሃለሁ ÷ ነገር ፡ ግን ፡
፲፫ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አላስጨንቅህም ። አሁ
ንም ፡ ቀንበሩን ፡ ከአንተ ፡ እሰብራለሁ ÷ እስራ
ትህንም ፡ እበጥሳለሁ ።
፲፬ እግዚአብሔርም ፡ ከስምህ ፡ ማንም ፡ ከእንግ
ዲህ ፡ ወዲህ ፡ እንዳይዘራ ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ አዝዞ
አል ፤ ከአምላኮችህ ፡ ቤት ፡ የተቀረጸውንና ፡
ቀልጦ ፡ የተሠራውን ፡ ምስል ፡ አጠፋለሁ ፤
አንተም ፡ የተጠቃህ ፡ ነህና ፡ መቃብርህን ፡
እምሳለሁ ።
፲፭ እነሆ ÷ የምስራችን ፡ የሚያመጣ ፡ ሰላምንም ፡
የሚያወራ ፡ ሰው ፡ እግር ፡ በተራሮች ፡ ላይ ፡
ነው ! ይሁዳ ፡ ሆይ ÷ አጥፊው ፡ ፈጽሞ ፡ ጠፍ
ቶአልና ÷ ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ በአንተ ፡
ዘንድ ፡ አያልፍምና ፡ ዓመት ፡ በዓሎችህን ፡
አድርግ ÷ ስእለቶችህን ፡ ክፈል ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ የሚቀጠቅጥ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ወጥቶአል ፤
ምሽግን ፡ ጠብቅ ÷ መንገድንም ፡ ሰልል ፤ ወገ
ብህን ፡ አጽና ÷ ኃይልህንም ፡ እጅግ ፡ አበርታ ።
፪ ዘራፊዎች ፡ ዘርፈዋቸዋልና ÷ የወይናቸውንም ፡
አረግ ፡ አጥፍተዋልና ፡ እግዚአብሔር ፡ የያዕ
ቆብን ፡ ክብር ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ ክብር ፡ ይመ
፫ ልሳል ። የኃያላኑ ፡ ጋሻ ፡ ቀልቶአል ÷ ጽኑዓንም ፡
ቀይ ፡ ልብስ ፡ ለብሰዋል ። እርሱም ፡ በሚያዘጋ

ጅበት ፡ ቀን ፡ ሰረገሎች ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ይንቦገ
፬ ቦጋሉ ፤ የጦሩም ፡ ሶመያ ፡ ይወዛወዛል ። ሰረገ
ሎች ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ ይነጕዳሉ ፥ አደባባ
ይም ፡ ይጋጫሉ ፤ መልክቸው ፡ እንደ ፡ ፋና ፡
፭ ነው ፥ እንደ ፡ መብረቅም ፡ ይከንፋሉ ። መሳ
ፍንቱን ፡ ያስባል ፤ በአረማመዳቸው ፡ ይሰናከ
ላሉ ፤ ፈጥነው ፡ በቅጥርዋ ፡ ላይ ፡ ይወጣሉ ፥
፮ መጠጊያም ፡ ተዘጋጀለት ። የወንዞቹም ፡ መዝ
ጊያዎች ፡ ተከፈቱ ፥ የንጉሡ ፡ ቤትም ፡ ቀለ
፯ ጠች ። ንግሥት ፡ ተገለጠች ፥ ተማረከችም ፥
ሴቶች ፡ ባሪያዎችዋም ፡ እንደ ፡ ርግብ ፡ እየጮ
ኹና ፡ ደረታቸውን ፡ እየመቱ ፡ ዋይ ፡ ዋይ ፡
ይላሉ ።

፰ ነነዌ ፡ ግን ፡ ከዱሮ ፡ ዘመን ፡ ጀምራ ፡ እንደ ፡
ተከማቸ ፡ ውኃ ፡ ነበረች ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ይሸ
ሻሉ ፤ እነርሱም ፡— ቁሙ ፥ ቁሙ ፡ ይላሉ ፥
፱ ነገር ፡ ግን ፡ የሚመለስ ፡ የለም ። መዝገብዋ ፡
መጨረሻ ፡ የለውምና ፥ የከበረውም ፡ የዕቃዋ ፡
ሁሉ ፡ ብዛት ፡ አይቈጠርምና ፡ ብሩን ፡ በዝብዙ ፥
፲ ወርቁንም ፡ በዝብዙ ። ባዶና ፡ ባድማ ፡ ምድረ ፡
በዳም ፡ ሆናለች ፤ ልብ ፡ ቀልጦአል ፥ ጕልበቶ
ችም ፡ ተብረከረከዋል ፤ በወገብም ፡ ሁሉ ፡
ሕማም ፡ አለ ፥ የሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ጠቍሮ
፲፩ አል ። የአንበሶችም ፡ መደብ ፥ የአንበሶችም ፡
ደቦል ፡ የሚሰማራበት ፥ አንበሳውና ፡ አንበ
ሳይቱ ፡ ግልገሉም ፡ ሳይፈሩ ፡ የሚሄዱት ፡
፲፪ ስፍራ ፡ ወዴት ፡ ነው ? አንበሳው ፡ ለልጆቹ ፡
የሚበቃውን ፡ ነጠቀ ፥ ለእንስቶቹም ፡ ሰበረላ
ቸው ፡ ዋሻውን ፡ በንጥቂያ ፥ መደቡንም ፡ በቅ
፲፫ ሚያ ፡ ሞልቶታል ። እነሆ ፡ በአንቺ ፡ ላይ ፡ ነኝ ፥
ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ ሰረገ
ሎችዋንም ፡ አቃጥዬ ፡ አጤሳለሁ ፥ ሰይፍም ፡
የአንበሳ ፡ ደቦሎችሽን ፡ ይበላቸዋል ፤ ንጥቂያሽ
ንም ፡ ከምድር ፡ አጠፋለሁ ፥ የመልክተኞች
ሽን ፡ ድምፅ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አይሰማም ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ለደም ፡ ከተማ ፡ ወዮላት ! በሁለንተናዋ ፡
ሐሰትና ፡ ቅሚያ ፡ ሞልቶበታል ፤ ንጥቂያ ፡ ከእ
፪ ርስዋ ፡ አያልቅም ። የአለንጋ ፡ ድምፅ ፥ የመን
ኰራኵርም ፡ ድምፅ ፥ የፈረሶችም ፡ ኰቴ ፥ የፈ
፫ ጣን ፡ ሰረገላም ፡ ጩኸት ፡ ተሰምቶአል ፤ ፈረሰ
ኛው ፡ ይጋልባል ፥ ሰይፍም ፡ ይንቦገቦጋል ፥
ጦርም ፡ ይብለጨለጫል ፤ የተገደሉትም ፡ ይበ
ዛሉ ፥ በድኖችም ፡ በክምር ፡ ይከመራሉ ፥ ሬሳ
ቸውም ፡ አይቈጠርም ፤ በሬሳቸውም ፡ ይሰናከ
፬ ላሉ ። ስለ ፡ ተዋበችው ፡ ጋለሞታ ፡ ግልሙ
ትና ፡ ብዛት ፡ ይህ ፡ ሆኖአል ፤ እርስዋም ፡ በመ
ተትዋ ፡ እጅግ ፡ በለጠች ፥ አሕዛብንም ፡ በግል
ሙትናዋ ፥ ወገኖችንም ፡ በመተትዋ ፡ ሸጠች ።
፭ እነሆ ፥ በአንቺ ፡ ላይ ፡ ነኝ ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥ ልብስሽን ፡ በፊትሽ ፡ እገ
ልጣለሁ ፤ ኀፍረተ ፡ ሥጋሽንም ፡ ለአሕዛብ ፥
፮ ነውርሽንም ፡ ለመንግሥታት ፡ አሳያለሁ ። ርኵ
ሰትንም ፡ በላይሽ ፡ እጥላለሁ ፥ እንቅሽማለሁ ፥
፯ ማላገጫም ፡ አደርግሻለሁ ። የሚያይሽም ፡ ሁሉ ፡
ከአንቺ ፡ ሸሽቶ ፡— ነነዌ ፡ ባድማ ፡ ሆናለች ፤
የሚያለቅስላትስ ፡ ማን ፡ ነው ? የሚያጽናናት
ንስ ፡ ከወዴት ፡ እፈልጋለሁ ? ይላል ።

፰ አንቺ ፡ በመስኖች ፡ መካከል ፡ ከተቀመጠ
ችው ፥ ውኃም ፡ በዙሪያዋ ፡ ከነበራት ፥ ምሽግ
ዋም ፡ ባሕር ፡ ከነበረ ፥ ቅጥርዋም ፡ በባሕር ፡
ውስጥ ፡ ከነበረ ፡ ከኖእ ፡ አሞን ፡ ትበልጫለሽን ?
፱ ኢትዮጵያና ፡ ግብጽ ፡ የማይቈጠር ፡ ኃይልዋ ፡
፲ ነበሩ ፤ ፉጥና ፡ ልብያ ፡ ረዳቶችዋ ፡ ነበሩ ። እር
ስዋ ፡ ግን ፡ ተማርካ ፡ ፈለሰች ፤ ሕፃናቶችዋ ፡
በመንገድ ፡ ሁሉ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ተፈጠፈጡ ፤ በከ
በርቴዎችዋም ፡ ላይ ፡ ዕጣ ፡ ተጣጣሉ ፥ ታላላ
፲፩ ቆችዋም ፡ ሁሉ ፡ በሰንሰለት ፡ ታሰሩ ። አንቺም ፡
ትሰክሪአለሽ ፡ ወራዳም ፡ ትሆኚለሽ ፤ አንቺ ፡
ደግሞ ፡ ከጠላት ፡ የተነሣ ፡ መጠጊያን ፡ ትፈል
፲፪ ጊአለሽ ። አምባሽ ፡ ሁሉ ፡ የመጀመሪያውን ፡
የበሰለ ፡ ፍሬ ፡ እንደ ፡ ያዙ ፡ እንደ ፡ በለስ ፡ ዛፎች ፡
ነው ፤ ቢወዛወዝ ፡ በሚበላው ፡ አፍ ፡ ውስጥ ፡
፲፫ ይወድቃል ። እነሆ ፥ በመካከልሽ ፡ ያሉ ፡ ሕዝ
ብሽ ፡ ሴቶች ፡ ናቸው ፤ የአገርሽ ፡ በሮች ፡ ለጠ
ላቶችሽ ፡ ፈጽሞ ፡ ተከፍተዋል ፥ እሳትም ፡ መወ
፲፬ ርወሪያዎችህን ፡ በልቶአል ። ከብበው ፡ ያስ
ጨንቁሻልና ፡ ውኃን ፡ ቅጂ ፤ አምባሽን ፡ አጠ
ንክሪ ፤ ወደ ፡ ጭቃ ፡ ገብተሽ ፡ እርገጪ ፤ የጡ
፲፭ ብን ፡ መሥሪያ ፡ ያዢ ። በዚያ ፡ እሳት ፡ ይበላ
ሻል ፥ ሰይፍ ፡ ያጠፋሻል ፥ እንደ ፡ ደጎብያ ፡
ይበላሻል ፤ እንደ ፡ ደጎብያ ፡ ብዢ ፥ እንደ ፡ አን
፲፮ በጣም ፡ ተበዢ ። ነጋዴዎችሽን ፡ ከሰማይ ፡ ከዋ
ክብት ፡ ይልቅ ፡ አበዛሽ ፤ ደጎብያ ፡ ተዘረጋ ፥
፲፯ በረረም ። በአንቺ ፡ ዘንድ ፡ ዘውድ ፡ የጫኑት ፡
እንደ ፡ አንበጣ ፥ አለቆችሽም ፡ እንደሚንቀሳ
ቀሱ ፡ ኵብኵባዎች ፡ ናቸው ፤ በብርድ ፡ ቀን ፡
በቅጥር ፡ ውስጥ ፡ ይቀመጣሉ ፥ ፀሐይም ፡ በወ
ጣች ፡ ጊዜ ፡ ያኰበኵባሉ ፤ ስፍራቸው ፡ በየት ፡
፲፰ እንደ ፡ ሆነ ፡ አይታወቅም ። የአሦር ፡ ንጉሥ ፡
ሆይ ፥ እረኞችህ ፡ አንቀላፍተዋል ፤ መኳንንቶ
ችህም ፡ ዐርፈዋል ፤ ሕዝብህም ፡ በተራሮች ፡
ላይ ፡ ተበትኖአል ፥ የሚሰበስበውም ፡ የለም ።
፲፱ ስብራትህ ፡ አይፈወስም ፥ ቍስልህም ፡ ክፉ ፡
ነው ፤ ወሬህንም ፡ የሚሰሙ ፡ ሁሉ ፡ እጃቸውን ፡
በአንተ ፡ ላይ ፡ ያጨበጭባሉ ፤ ክፋትህ ፡ ሁል
ጊዜ ፡ ያላለፈችበት ፡ ሰው ፡ ማን ፡ ነውና ?

# ትንቢተ ፡ ዕንባቆም ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ ነቢዩ ፡ ዕንባቆም ፡ ያየው ፡ ሸክም ፡ ይህ ፡ ነው ።
፪ አቤቱ ÷ እኔ ፡ ስጮኽ ፡ የማትሰማው ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ? ስለ ፡ ግፍ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እጮኻለሁ ÷ አንተም ፡ አታድንም ። ፫ በደልንስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አሳየኸኝ ? ጠማምነትንስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትመለከታለህ ? ጥፋትና ፡ ግፍ ፡ በፊቴ ፡ ነው ፤ ጠብና ፡ ክርክር ፡ ይነሣሉ ። ፬ ስለዚህ ፡ ሕግ ፡ ላልቶአል ÷ ፍርድም ፡ ድል ፡ ነሥቶ ፡ አይወጣም ፤ ኃጢአተኛ ፡ ጻድቅን ፡ ይከብባልና ፤ ስለዚህ ፡ ፍርድ ፡ ጠማማ ፡ ሆኖ ፡ ይወጣል ።
፭ እናንተ ፡ የምትንቁ ፡ ሆይ ÷ አንድ ፡ ቢተርክላችሁ ፡ ስንኳ ፡ የማታምኑትን ፡ ሥራ ፡ በዘመናችሁ ፡ እሠራለሁና ፡ እዩ ÷ ተመልከቱ ÷ ተደነቁ ። ፮ እነሆ ÷ የእነርሱ ፡ ያልሆነውን ፡ መኖሪያ ፡ ይወርሱ ፡ ዘንድ ፡ በምድር ፡ ስፋት ፡ ላይ ፡ የሚሄዱትን ፡ መራሮችንና ፡ ፈጣኖችን ፡ ሕዝብ ፡ ከለዳውያንን ፡ አስነሣለሁ ። ፯ እነርሱ ፡ የሚያስፈሩና ፡ የሚያስደነግጡ ፡ ናቸው ፤ ፍርዳቸውና ፡ ክብራቸው ፡ ከራሳቸው ፡ ይወጣል ። ፰ ፈረሶቻቸውም ፡ ከነብር ፡ ይልቅ ፡ ፈጣኖች ፡ ናቸው ÷ ከማታም ፡ ተኵላ ፡ ይልቅ ፡ ጨካኞች ፡ ናቸው ፤ ፈረሰኞቻቸውም ፡ ይንሳፈፋሉ ÷ ከሩቅም ፡ ይመጣሉ ÷ ለመብልም ፡ እንደሚቸኵል ፡ ንስር ፡ ይበርራሉ ። ፱ ሁሉም ፡ ለግፍ ፡ ሥራ ፡ ይመጣሉ ÷ ፊታቸውንም ፡ እንደ ፡ ምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ ያቀናሉ ፤ ምርኮኞችንም ፡ እንደ ፡ አሸዋ ፡ ይሰበስባሉ ። ፲ በነገሥታት ፡ ላይ ፡ ያላግጣሉ ÷ መሳፍንትም ፡ ቀዛ ፡ ሆነውላቸዋል ፤ በምሽጉ ፡ ሁሉ ፡ ይስቃሉ ÷ አፈሩንም ፡ ከምረው ፡ ይወስዱታል ። ፲፩ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ እንደ ፡ ነፋስ ፡ አልፎ ፡ ይሄዳል ÷ ይበድልማል ፤ ኃይሉንም ፡ አምላክ ፡ ያደርገዋል ።
፲፪ አቤቱ ÷ የተቀደስህ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ÷ አንተ ፡ ከዘላለም ፡ ጀምሮ ፡ አልነበርህምን ? እኛ ፡ አንሞትም ፤ አቤቱ ÷ ለፍርድ ፡ ሠርተኸዋል ÷ ለተግሣጽም ፡ አድርገኸዋል ። ፲፫ ዓይኖችህ ፡ ክፉ ፡ እንዳያዩ ፡ ንጹሐን ፡ ናቸው ÷ ጠማምነትንም ፡ ትመለከት ፡ ዘንድ ፡ አትችልም ፤ አታላዮችንስ ፡ ለምን ፡ ትመለከታለህ ? ኃጢአተኛውስ ፡ ከእርሱ ፡ ይልቅ ፡ ጻድቅ ፡ የሆነውን ፡ ሲውጠው ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ዝም ፡ ትላለህ ? ፲፬ ሰዎችንም ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ ዓሣዎች ÷ አለቃም ፡ እንደሌላቸው ፡ ተንቀሳቃሾች ፡ ለምን ፡ ታደርጋቸዋለህ ? ፲፭ ሁሉን ፡ በመቃጥን ፡ ያወጣል ÷ በመረቡም ፡ ይይዛቸዋል ÷ በአሽክላውም ፡ ውስጥ ፡ ያከማቻቸዋል ፤ ስለዚህ ፡ ደስ ፡ እያለው ፡ እልል ፡ ይላል ። ፲፮ እድል ፈንታው ፡ በእነርሱ ፡ ሰብታለችና ÷ መብሉም ፡ በዝቶአልና ፡ ስለዚህ ፡ ለመረቡ ፡ ይሠዋል ÷ ለአሽክላውም ፡ ያጥናል ። ፲፯ ስለዚህ ፡ መረቡን ፡ ይጥላልን ? አሕዛብንም ፡ ዘወትር ፡ ይገድል ፡ ዘንድ ፡ አይራራምን ?

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ በመጠበቂያዬ ፡ ላይ ፡ እቆማለሁ ÷ በአምባ ፡ ላይም ፡ እወጣለሁ ፤ የሚናገረኝንም ÷ ስለ ፡ ክርክሬም ፡ የምመልሰውን ፡ አውቅ ፡ ዘንድ ፡ እመለከታለሁ ። ፪ እግዚአብሔርም ፡ መለሰልኝ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—አንባቢው ፡ ይፈጥን ፡ ዘንድ ፡ ራእዩን ፡ ጻፍ ÷ በጽላትም ፡ ላይ ፡ ግለጠው ። ፫ ራእዩ ፡ ገና ፡ እስከ ፡ ተወሰነው ፡ ጊዜ ፡ ነው ÷ ወደ ፡ ፍጻሜውም ፡ ይቸኩላል ÷ እርሱም ፡ አይዋሽም ፤ ቢዘገይም ፡ በእርግጥ ፡ ይመጣልና ፡ ታገሠው ፤ እርሱ ፡ አይዘገይም ።
፬ እነሆ ÷ ነፍሱ ፡ ኰርታለች ÷ በውስጡም ፡ ቅን ፡ አይደለችም ፤ ጻድቅ ፡ ግን ፡ በእምነቱ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራል ። ፭ እርሱ ፡ አታላይና ፡ ኩሩ ፡ ሰው ፡ ነው ፤ በስፍራው ፡ ዐርፎ ፡ አይቀመጥም ፤ ስስቱን ፡ እንደ ፡ ሲኦል ፡ ያሰፋል ÷ እርሱም ፡ እንደ ፡ ሞት ፡ አይጠግብም ፤ አሕዛብንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ይሰበስባል ÷ ወገኖቹንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ያከማቻል ። ፮ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡—ለእርሱ ፡ ያልሆነውን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ለሚሰበስብ ፡ መያዣውንም ፡ ለራሱ ፡ የሚያበዛ ፡ ወዮለት ! እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ? እያሉ ፡ ምሳሌ ፡ አይመስሉብትምን ? ተረትም ፡ አይተርቱበትምን ? ፯ የሚነክሱህ ፡ ድንገት ፡ አይነሡብህምን ? የሚያስጨንቁህም ፡ ይነቃሉ ፤ ለእነርሱም ፡ ብዝበዛ ፡ ትሆናለህ ። ፰ የሰውን ፡ ደም ፡ ስላፈሰስህ ÷ በምድሪቱና ፡ በከተማይቱም ፡ በእርስዋም ፡ በሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ስላደረግኸው ፡ ግፍ ÷ አንተ ፡ ብዙዎችን ፡ አሕዛብን ፡ በዝብዘሃልና ፡ ከአሕዛብ ፡ የቀሩት ፡ ሁሉ ፡ ይበዘብዙሃል ።
፱ ከክፉ ፡ እንዲድን ፡ ጐጆውን ፡ በከፍታ ፡ ላይ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ለቤቱ ፡ ክፉ ፡ ትርፍን ፡ ለሚሰበስብ ፡ ወዮለት ! ፲ ብዙ ፡ አሕዛብን ፡ አጥፍተሃልና ፡ ለቤትህ ፡ እፍረትን ፡ መክረሃል ÷ በነፍስህም ፡ ላይ ፡ ኃጢአትን ፡ አድርገሃል ። ፲፩ ድንጋይም ፡ ከግንብ ፡ ውስጥ ፡ ይጮኻል ÷ እንጨትም ፡ ከውቅር ፡ ውስጥ ፡ ይመልስለታል ።
፲፪ ከተማን ፡ በደም ፡ ለሚሠራ ÷ ከተማንም ፡ በኃጢአት ፡ ለሚመሠርት ፡ ወዮለት ! ፲፫ እነሆ ÷ አሕዛብ ፡ ስለ ፡ እሳት ፡ እንዲሠሩ ÷ ወገኖችም ፡ ስለ ፡ ከንቱነት ፡ እንዲደክሙ ፡ ከሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የሆነ ፡ አይደለምን ? ፲፬ ውኃ ፡ ባሕርን ፡ እንደሚከድን ፡ ምድር ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ክብር ፡ በማወቅ ፡ ትሞላለችና ።
፲፭ ኀፍረተ ፡ ሥጋውን ፡ ለማየት ፡ ባልንጀራውን ፡ ለሚያጠጣ ÷ ክፉንም ፡ ለሚጨምርበት ÷

፲፮፤ ለሚያሰክረውም ፡ ወዮለት ! በክብር ፡ ፋንታ ፡ እፍረት ፡ ሞልቶብሃል ፤ አንተ ፡ ደግሞ ፡ ጠጥተህ ፡ ተንገድገድ ፤ የእግዚአብሔር ፡ የቀኙ ፡ ጽዋ ፡ ይመለስብሃል ፥ እፍረትም ፡ በክብርህ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ።
፲፯፤ የሰውንም ፡ ደም ፡ ስላፈሰስህ ፥ በምድሪቱና ፡ በከተማይቱም ፡ በእርስዋም ፡ በሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ስላደረግኸው ፡ ግፍ ፥ በሊባኖስ ፡ ላይ ፡ የሠራኸው ፡ ግፍ ፡ ይከድንሃል ፤ የአራዊትም ፡ አደጋ ፡ ያስፈራራሃል ።
፲፰፤ የተቀረጸውን ፡ ምስል ፡ ሠሪው ፡ የቀረጸው ፡ ለምን ፡ ጥቅም ፡ ነው ? ዲዳንም ፡ ጣዖት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ሠሪው ፡ የታመነበቱ ፥ ሐሰትን ፡ የሚያስተምር ፡ ቀልጦ ፡ የተሠራ ፡ ምን ፡ ይጠቅማል ?
፲፱፤ እንጨቱን ፡ — ንቃ ፥ ዲዳውንም ፡ ድንጋይ ፡ — ተነሣ ፡ ለሚለው ፡ ወዮለት ! በውኑ ፡ ይህ ፡ ያስተምራልን ? እነሆ ፥ በወርቅና ፡ በብር ፡ ተለብጦአል ፥ ምንም ፡ እስትንፋስ ፡ የለበትም ።
፳፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በተቀደሰ ፡ መቅደሱ ፡ አለ ! ምድርም ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ዝም ፡ ትበል ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፤ የነቢዩ ፡ የዕንባቆም ፡ ጸሎት ፡ በመዝሙር ።
፪፤ አቤቱ ፥ ዝናህን ፡ ሰምቼ ፡ ፈራሁ ፤
አቤቱ ፥ በዓመታት ፡ መካከል ፡ ሥራህን ፡ ፈጽም ፤
በዓመታት ፡ መካከል ፡ ትታወቅ ፤
በመዓት ፡ ጊዜ ፡ ምሕረትን ፡ አስብ ።
፫፤ እግዚአብሔር ፡ ከቴማን ፥
ቅዱሱም ፡ ከፋራን ፡ ተራራ ፡ ይመጣል ።
ክብሩ ፡ ሰማያትን ፡ ከድኖአል ፥
ምስጋናውም ፡ ምድርን ፡ ሞልቶአል ።
፬፤ ፀዳሉም ፡ እንደ ፡ ብርሃን ፡ ነው ፤
ጨረር ፡ ከእጁ ፡ ወጥቶአል ፤
ኃይሉም ፡ በዚያ ፡ ተሰውሮአል ።
፭፤ ቸነፈር ፡ በፊቱ ፡ ይሄዳል ፥
የእሳትም ፡ ነበልባል ፡ ከእግሩ ፡ ይወጣል ።
፮፤ ቆመ ፥ ምድርንም ፡ አወከት ፤
ተመለከተ ፥ አሕዛብንም ፡ አናወጠ ፤
የዘላለምም ፡ ተራሮች ፡ ተቀጠቀጡ ፥
የዘላለምም ፡ ኮረብቶች ፡ ቀለጡ ፤
መንገዱ ፡ ከዘላለም ፡ ነው ።
፯፤ የኢትዮጵያ ፡ ድንኳኖች ፡ ሲጨነቁ ፡ አየሁ ፤
የምድያም ፡ አገር ፡ መጋረጃዎች ፡ ተንቀጠቀጡ ።
፰፤ በውኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ በወንዞች ፡ ላይ ፡ ተቈጥቶአልን ?
ቍጣህ ፡ በወንዞች ፡ ላይ ፥ መዓትህም ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡ ነውን ?
በፈረሶችህና ፡ በማዳንህ ፡ ሰረገሎች ፡ ላይ ፡ ተቀምጠሃልና ።
፱፤ በቃልህ ፡ እንደ ፡ ማልህ ፡
መቅሠፍትህን ፡ አወጣህ ፤ ቀስትህንም ፡ ገተርህ ፤
ምድርን ፡ ሰንጥቀህ ፡ ፈሳሾችን ፡ አወጣህ ።
፲፤ ተራሮች ፡ አንተን ፡ አይተው ፡ ተጨነቁ ፤
የውኃ ፡ ሞገድ ፡ አልፎአል !
ቀላዩም ፡ ድምፁን ፡ ሰጥቶአል ፥
እጁንም ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ አንሥቶአል ።
፲፩፤ ፍላጾችህ ፡ ከወጡበት ፡ ብርሃን ፡ የተነሣ ፥
ከሚንበገበገውም ፡ ከጦርህ ፡ ፀዳል ፡ የተነሣ ፥
ፀሐይና ፡ ጨረቃ ፡ በመኖሪያቸው ፡ ቆሙ ።
፲፪፤ በምድር ፡ ላይ ፡ በመዓት ፡ ተራመድህ ፤
አሕዛብን ፡ በቍጣ ፡ አኼድሃቸው ።
፲፫፤ ሕዝብህን ፡ ለመታደግ ፥
የቀባኸውንም ፡ ለማዳን ፡ ወጣህ ፤
የኃጢአተኛውን ፡ ቤት ፡ ራስ ፡ ቀጠቀጥህ ፤
መሠረቱን ፡ እስከ ፡ አንገቱ ፡ ድረስ ፡ ገለጥህ ።
፲፬፤ የአለቆችን ፡ ራስ ፡ በገዛ ፡ በትራቸው ፡ ወጋህ ፤
እኔን ፡ ይበትኑ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ መጡ ፤
ችግረኛውን ፡ በስውር ፡ ለመዋጥ ፡ ደስታቸው ፡ ነው ።
፲፭፤ ፈረሶችህን ፡ በባሕር ፥
በብዙ ፡ ውኆችም ፡ ላይ ፡ አስረገጥህ ።

፲፮፤ እኔ ፡ ሰምቻለሁ ፥ ልቤም ፡ ደነገጠብኝ ፤
ከድምፁ ፡ የተነሣ ፡ ከንፈሮቼ ፡ ተንቀጠቀጡ ፤
መንቀጥቀጥ ፡ ወደ ፡ አጥንቶቼ ፡ ውስጥ ፡ ገባ ፤
በስፍራዬ ፡ ሆኜ ፡ ተናወጥሁ ፤
በሚያስጨንቁን ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡
የመከራን ፡ ቀን ፡ ዝም ፡ ብዬ ፡ እጠብቃለሁ ።
፲፯፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ በለስም ፡ ባታፈራ ፥
በወይንም ፡ ሐረግ ፡ ፍሬ ፡ ባይገኝ ፥
የወይራ ፡ ሥራ ፡ ቢጐድል ፥
እርሾችም ፡ መብልን ፡ ባይሰጡ ፥
በጎች ፡ ከበረቱ ፡ ቢጠፉ ፥
ላሞችም ፡ በጋጡ ፡ ውስጥ ፡ ባይገኙ ፥
፲፰፤ እኔ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፤
በመድኃኒቴ ፡ አምላክ ፡ ሐሤት ፡ አደርጋለሁ ።
፲፱፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኃይሌ ፡ ነው ፤
እግሮቼን ፡ እንደ ፡ ዋላ ፡ እግሮች ፡ ያደርጋል ፤
በከፍታዎችም ፡ ላይ ፡ ያስሄደኛል ።

# ት ን ቢ ተ ፡ ሶ ፎ ን ያ ስ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በአሞጽ ፡ ልጅ ፡ በኢዮስ
ያስ ፡ ዘመን ፡ ወደ ፡ ሕዝቅያስ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡
አማርያ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ጎዶልያስ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡
ኵሲ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ሶፎንያስ ፡ የመጣ ፡ የእግዚ
አብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ።
፪፤ ነገርን ፡ ሁሉ ፡ ከምድር ፡ ፊት ፡ ፈጽሜ ፡ አጠ
፫፤ ፋለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። ሰውንና ፡
እንስሳን ፡ አጠፋለሁ ፤ የሰማይን ፡ ወፎችና ፡
የባሕርን ፡ ዓሣዎች ፡ ማሰናከያንም ፡ ከኃጢ
አተኞች ፡ ጋር ፡ አጠፋለሁ ፤ ሰውንም ፡ ከም
ድር ፡ ፊት ፡ እቈርጣለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብ
፬፤ ሔር ። እጄንም ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ በኢየሩሳሌ
ምም ፡ በሚኖሩት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እዘረጋለሁ ፤
ከዚህም ፡ ስፍራ ፡ የበአልን ፡ ቅሬታና ፡ የጣዖ
፭፤ ታቱን ፡ ካህናት ፡ ስም ፡ አጠፋለሁ ፤ በሰገነትም ፡
ላይ ፡ ለሰማይ ፡ ሠራዊት ፡ የሚሰግዱትን ፥ በእ
ግዚአብሔርና ፡ በንጉማቸው ፡ በሚልኮም ፡
፮፤ ምለው ፡ የሚሰግዱትን ፥ እግዚአብሔርንም ፡
ከመከተል ፡ የተመለሱትን ፥ እግዚአብሔር
ንም ፡ ያልፈለጉትንና ፡ ያልጠየቁትን ፡ አጠፋ
ለሁ ።
፯፤ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ቀርቦአልና ፥ እግዚአ
ብሔር ፡ መሥዋዕትን ፡ አዘጋጅቶአልና ፥ የጠ
ራቸውንም ፡ ቀድሶአልና ፡ በጌታ ፡ በእግዚአብ
፰፤ ሔር ፡ ፊት ፡ ዝም ፡ በሉ ። በእግዚአብሔርም ፡
መሥዋዕት ፡ ቀን ፡ አለቆችንና ፡ የንጉሥን ፡
ልጆች ፡ እንግዳ ፡ ልብስ ፡ የሚለብሱትንም ፡
፱፤ ሁሉ ፡ እቀጣለሁ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ በመድረኩ ፡
ላይ ፡ የሚዘልሉትን ፥ የጌታቸውን ፡ ቤት ፡ ዓመ
ፃንና ፡ ሽንገላን ፡ የሚሞሉትን ፡ እቀጣለሁ ።
፲፤ በዚያ ፡ ቀን ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፥ ከዓ
ሣው ፡ በር ፡ የጩኸት ፡ ድምፅ ፥ ከከተማውም ፡
በሁለተኛው ፡ ክፍል ፡ ውካታ ፥ ከኮረብቶቹም ፡
፲፩፤ ታላቅ ፡ ሽብር ፡ ይሆናል ። እናንተ ፡ በመክቴሽ ፡
የምትኖሩ ፡ ሆይ ፥ የከነዓን ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡
ጠፍተዋልና ፥ ብርም ፡ የተሸከሙ ፡ ሁሉ ፡ ተቈ
፲፪፤ ርጠዋልና ፡ አልቅሱ ። በዚያም ፡ ዘመን ፡ ኢየ
ሩሳሌምን ፡ በመብራት ፡ እመረምራለሁ ፤ በአ
ተላቸውም ፡ ላይ ፡ የሚቀመጡትን ፥ በልባቸ
ውም ፡— እግዚአብሔር ፡ መልካምን ፡ አያደር
ግም ፥ ክፉም ፡ አያደርግም ፡ የሚሉትን ፡ ሰዎች ፡
፲፫፤ እቀጣለሁ ። ብልጥግናቸውም ፡ ለምርኮ ፡ ይሆ
ናል ፥ ቤቶቻቸውም ፡ ይፈርሳሉ ፤ ቤቶችንም ፡
ይሠራሉ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አይቀመጡባቸውም ፤
ወይንንም ፡ ይተክላሉ ፥ የወይን ፡ ጠጁን ፡ ግን ፡
አይጠጡም ።
፲፬፤ ታላቁ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ቀርቦአል ፤
የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ድምፅ ፡ ቀርቦአል ፡ እጅ
ግም ፡ ፈጥኖአል ፤ ኃያሉም ፡ በዚያ ፡ በመራራ ፡
፲፭፤ ልቅሶ ፡ ይጮኻል ። ያ ፡ ቀን ፡ የመዓት ፡ ቀን ፥
የመከራና ፡ የጭንቀት ፡ ቀን ፥ የመፍረስና ፡ የመ
ጥፋት ፡ ቀን ፥ የጨለማና ፡ የጭጋግ ፡ ቀን ፥ የደ
፲፮፤ መናና ፡ የድቅድቅ ፡ ጨለማ ፡ ቀን ፥ በተመሸጉ ፡
ከተሞችና ፡ በረዘሙ ፡ ግንቦች ፡ ላይ ፡ የመለከ
፲፯፤ ትና ፡ የሰልፍ ፡ ጩኸት ፡ ቀን ፡ ነው ። በእግዚ
አብሔርም ፡ ላይ ፡ ኃጢአት ፡ ሠርተዋልና ፡
እንደ ፡ ዕውር ፡ እስኪሄዱ ፡ ድረስ ፡ ሰዎችን ፡
አስጨንቃለሁ ፤ ደማቸውም ፡ እንደ ፡ ትቢያ ፥
፲፰፤ ሥጋቸውም ፡ እንደ ፡ ጕድፍ ፡ ይፈስሳል ። በእ
ግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ ቀን ፡ ብራቸውና ፡ ወር
ቃቸው ፡ ሊያድናቸው ፡ አይችልም ፤ እርሱም ፡
በምድር ፡ የሚኖሩትን ፡ ሁሉ ፡ ፈጥኖ ፡ ይጨርሳ
ቸዋልና ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ በቅንዓቱ ፡ እሳት ፡
ትበላለች ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፤፪፤ እናንተ ፡ እፍረት ፡ የሌላችሁ ፡ ሕዝብ ፡ ሆይ ፥
ትእዛዝ ፡ ሳይወጣ ፥ ቀኑም ፡ እንደ ፡ ገለባ ፡ ሳያ
ልፍ ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ ትኵሳት ፡
ሳይመጣባችሁ ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡
ቀን ፡ ሳይደርስባችሁ ፡ ተሰብሰቡ ፥ ተከማቹም ።
፫፤ እናንተ ፡ ፍርዱን ፡ የጠበቃችሁ ፡ የምድር ፡
ትሑታን ፡ ሁሉ ፥ እግዚአብሔርን ፡ ፈልጉ ፤
ጽድቅንም ፡ ፈልጉ ፥ ትሕትናንም ፡ ፈልጉ ፤
ምናልባት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ ቀን ፡ ትሰ
ወሩ ፡ ይሆናል ።
፬፤ ጋዛ ፡ ትበረበራለች ፥ አስቀሎናም ፡ ባድማ ፡
ትሆናለች ፤ አዛጦንንም ፡ በቀትር ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡
፭፤ ያሳድዱአታል ፥ አቃሮንም ፡ ትነቀላለች ። በባ
ሕር ፡ ዳር ፡ ለሚኖሩ ፡ ለከሊታውያን ፡ ሕዝብ ፡
ወዮላቸው ! የፍልስጥኤማውያን ፡ ምድር ፡
ከነዓን ፡ ሆይ ፥ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በአንተ ፡
ላይ ፡ ነው ፥ የሚቀመጥብህም ፡ ሰው ፡ እንዳይኖር ፡
፮፤ አጠፋሃለሁ ። ቀርጤስም ፡ የእረኞች ፡ መኖሪያና ፡
፯፤ የመንጎች ፡ በረት ፡ ይሆናል ። የባሕሩም ፡ ዳር ፡
ለይሁዳ ፡ ቤት ፡ ቅሬታ ፡ ይሆናል ፥ በዚያም ፡
ይሰማራሉ ፤ አምላካቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ ይጐ
በኛቸዋልና ፥ ምርኮአቸውንም ፡ ይመልሳልና ፡
በአስቀሎና ፡ ቤቶች ፡ ውስጥ ፡ ማታ ፡ ይተኛሉ ።
፰፤ በሕዝቤም ፡ ላይ ፡ ያላገጡባትን ፥ በድንበራ
ቸውም ፡ ላይ ፡ እየታበዩ ፡ የተናገሩባትን ፡ የሞ
ዓብን ፡ ማላገጥና ፡ የአሞንን ፡ ልጆች ፡ ስድብ ፡
፱፤ ሰምቻለሁ ። ስለዚህ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡
የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፡— እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ በእርግጥ ፡ ሞዓብ ፡
እንደ ፡ ሰዶም ፥ የአሞንም ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ገሞራ ፥
የሳማ ፡ ስፍራና ፡ የጨው ፡ ጕድጓድ ፡ ለዘላለ
ምም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሆነው ፡ ይኖራሉ ፤ የሕዝ

ቤም ፡ ቅሬታ ፡ ይበዘብዛቸዋል ÷ ከወገኔም ፡
፲፡ የተረፉት ፡ ይወርሱአቸዋል ። በሠራዊት ፡ ጌታ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ አላግጠዋልና ተ
እየታበዩም ፡ ተናግረዋልና ፡ ይህ ፡ ስለ ፡ ትዕቢታ
፲፩፡ ቸው ፡ ያገኛቸዋል ። እግዚአብሔር ፡ በእነርሱ ፡
ላይ ፡ የተፈራ ፡ ይሆናል ÷ የምድርንም ፡ አማል
ክት ፡ ሁሉ ፡ ያከሳቸዋል ፤ በአሕዛብም ፡ ደሴ
ቶች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በስ
ፍራቸው ፡ ሆነው ፡ ለእርሱ ፡ ይሰግዳሉ ።
፲፪፡ እናንተም ፡ ኢትዮጵያውያን ፡ ደግሞ ÷ በሰ
፲፫፡ ይፌ ፡ ትገደላላችሁ ። እርሱም ፡ በሰሜን ፡ ላይ ፡
እጁን ፡ ይዘረጋል ÷ አሦርንም ፡ ያጠፋል ፤ ነነዌ
ንም ፡ ባድማ ÷ እንደ ፡ በረሃም ፡ ደረቅ ፡ ያደርጋ
፲፬፡ ታል ። መንጎችም ፡ የምድርም ፡ አራዊት ፡
ሁሉ ፡ በውስጥዋ ፡ ይመሰጋሉ ፤ ይብራና ፡ ጃርት ፡
በዓምዶችዋ ፡ መካከል ፡ ያድራሉ ፤ ድምፃቸው ፡
በመስኮቶችዋ ፡ ይጮኻል ፤ የዝግባም ፡ እን
ጨት ፡ ሥራ ፡ ይገለጣልና ፡ በመድረኮችዋ ፡
፲፭፡ ላይ ፡ ጥፋት ፡ ይሆናል ። ተዘልላ ፡ የተቀመጠች÷
በልብዋም ፡— እኔ ፡ ነኝ ÷ ከእኔም ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡
የለም ፡ ያለች ፡ ደስተኛይቱ ፡ ከተማ ፡ ይህች ፡
ናት ፤ አራዊት ፡ የሚመሰጉባት ፡ ባድማ ፡ እን
ዴት ፡ ሆነች ! በእርስዋ ፡ በኩል ፡ የሚያልፈው ፡
ሁሉ ፡ እጁን ፡ እያወዛወዘ ፡ ያፍዋጫል ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፡ ለዓመፀኛይቱና ፡ ለረከሰች ፡ ለአስጨናቂይ
፪፡ ቱም ፡ ከተማ ፡ ወዮላት ! ድምፅን ፡ አልሰማ
ችም ÷ ተግሣጽንም ፡ አልተቀበለችም ፤ በእግ
ዚአብሔርም ፡ አልታመነችም ÷ ወደ ፡ አምላክ
፫፡ ዋም ፡ አልቀረበችም ። በውስጥዋ ፡ ያሉ ፡ አለ
ቆችዋ ፡ እንደሚያገሡ ፡ አንበሶች ፡ ናቸው ፤
ፈራጆችዋም ፡ እስከ ፡ ነገ ፡ ድረስ ፡ ምንም ፡ እን
ደማያስቀሩ ፡ እንደ ፡ ማታ ፡ ተኵላዎች ፡ ናቸው ።
፬፡ ነቢያቶችዋ ፡ ቀሌታሞችና ፡ ተንኰለኞች ፡
ሰዎች ፡ ናቸው ፤ ካህናቶችዋም ፡ መቅደሱን ፡
አርክሰዋል ÷ በሕግም ፡ ላይ ፡ ግፍ ፡ ሠርተዋል ።
፭፡ እግዚአብሔር ፡ በውስጥዋ ፡ ጻድቅ ፡ ነው ፤ ክፋ
ትን ፡ አያደርግም ፤ ፍርዱን ፡ በየማለዳው ፡ ወደ ፡
ብርሃን ፡ ያወጣል ÷ ሳያወጣውም ፡ አይቀርም ፤
፮፡ ዓመፀኛው ፡ ግን ፡ እፍረትን ፡ አያውቅም ። አሕ
ዛብን ፡ አጥፍቻለሁ ፤ ግንቦቻቸው ፡ ሁሉ ፡ ፈር
ሰዋል ፤ መንገዳቸውን ፡ ማንም ፡ እንዳያልፍ
ባት ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ አድርጌአለሁ ÷ ከተሞቻ
ቸውም ፡ ማንም ፡ እንዳይኖርባቸው ÷ አን
ድስ ፡ እንኳ ፡ እንዳይቀመጥባቸው ፡ ፈርሰዋል ።
፯፡ እኔም — ይፈሩኛል ÷ ተግሣጽንም ፡ ይቀበላሉ ፤
ከዘዝኋትም ፡ ሁሉ ፡ ከዓይንዋ ፡ ምንም ፡ አይጠ
ፋም ፡ ብዬ ፡ ነበር ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ በማለዳ ፡ ተነ
ሥተው ፡ ድርጊታቸውን ፡ ሁሉ ፡ አረከሱ ።
፰፡ መዓቴንና ፡ የቍጣዬን ፡ ትኵሳት ፡ ሁሉ ፡ አፈ
ስስባቸው ፡ ዘንድ ፡ ፍርዴ ፡ አሕዛብን ፡ ለመሰብ
ሰብ ÷ መንግሥታትንም ፡ ለማከማቸት ፡ ነውና ÷
ምድርም ፡ ሁሉ ፡ በቅንዓቴ ፡ እሳት ፡ ትበላለ
ችና ፡ ስለዚህ ፡ ለመበዝበዝ ፡ እስከምነሣበት ፡
ቀን ፡ ድረስ ፡ ጠብቁኝ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።
፱፡ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡
ሆነው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያገለግሉት ፡ ዘንድ ፡
ስሙን ፡ እንዲጠሩ ፡ ንጹሕን ፡ ልሳን ፡ እመልስ
፲፡ ላቸዋለሁ ። ከኢትዮጵያ ፡ ወንዞች ፡ ማዶ ፡ የሚ
ማልዱኝ ÷ የተበተኑት ፡ ሴቶች ፡ ልጆቼ ÷ ቍር
፲፩፡ ባኔን ፡ ያመጡልኛል ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እየታ
በዩ ፡ የሚፎከሩትን ፡ ከመካከልሽ ፡ አወጣለሁና ÷
አንቺም ፡ በቅዱስ ፡ ተራራዬ ፡ ዳግመኛ ፡ አትኰ
ሪምና ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ተላልፈሽ ፡
፲፪፡ በሠራሽው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አታፍሪም ። በመካ
ከልሽም ፡ የዋህና ፡ ትሑት ፡ ሕዝብን ፡ አስቀ
ራለሁ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ስም ፡ ይታመናሉ ።
፲፫፡ የእስራኤል ፡ ቅሬታ ፡ ኃጢአትን ፡ አይሠሩም ÷
ሐሰትንም ፡ አይናገሩም ÷ በአፋቸውም ፡ ውስጥ ፡
ተንኰለኛ ፡ ምላስ ፡ አይገኝም ፤ እነርሱም ፡ ይሰ
ማራሉ ÷ ይመሰጉማል ÷ የሚያስፈራቸውም ፡
የለም ።
፲፬፡ የጽዮን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ ዘምሪ ፤ እስራኤል ፡
ሆይ ÷ እልል ፡ በል ፤ የኢየሩሳሌም ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷
በፍጹም ፡ ልብሽ ፡ ሐሤት ፡ አድርጊ ፡ ደስም ፡
፲፭፡ ይበልሽ ። እግዚአብሔር ፡ ፍርድሽን ፡ አስወ
ግዶአል ÷ ጠላትሽንም ፡ ጥሎአል ፤ የእስራ
ኤል ፡ ንጉሥ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመካከልሽ ፡
አለ ÷ ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡
፲፮፡ አታዩም ። በዚያን ፡ ቀን ፡ ለኢየሩሳሌም ፡—
ጽዮን ፡ ሆይ ÷ አትፍሪ ÷ እጆችሽም ፡ አይዛሉ ።
፲፯፡ አምላክሽ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመካከልሽ ፡ ታዳጊ ፡
ኃያል ፡ ነው ፤ በደስታ ፡ በአንቺ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ÷
በፍቅሩም ፡ ያርፋል ተ በእልልታም ፡ በአንቺ ፡
፲፰፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡ ይባላል ። ከጉባኤው ፡ ርቀው ፡
የሚያዝኑትን ÷ ከአንቺም ፡ የሆኑትን ፡ እሰበስ
ባለሁ ፤ ስድብ ፡ እንደ ፡ ሸክም ፡ ከብዶባቸው ፡
፲፱፡ ነበር ። በዚያ ፡ ዘመን ፡ እነሆ ÷ ባስጨነቁሽ ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ አደርግባቸዋለሁ ፤ አንካሳይቱንም ፡
አድናለሁ ÷ የተጣለችውንም ፡ እሰበስባታለሁ ፤
ባፈሩባትም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ለምስጋናና ፡
፳፡ ለክበረ ፡ ስም ፡ አደርጋቸዋለሁ ። በዚያ ፡ ዘመን ፡
አስገባችኋለሁ ÷ በዚያም ፡ ዘመን ፡ እሰበስባች
ኋለሁ ፤ ምርኮአችሁንም ፡ በዓይናችሁ ፡ ፊት ፡
በመለስሁ ፡ ጊዜ ፡ በምድር ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡
መካከል ፡ ለክበረ ፡ ስምና ፡ ለምስጋና ፡ አደርጋ
ችኋለሁ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

# ትንቢተ ፡ ሐጌ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ በንጉሡ ፡ በዳርዮስ ፡ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ በስድስተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በነቢዩ ፡ በሐጌ ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ አለቃ ፡ ወደ ፡ ሰላትያል ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ዘሩባቤል ፥ ወደ ፡ ታላቁም ፡ ካህን ፡ ወደ ፡ ኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢያሱ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ፪ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡— ይህ ፡ ሕዝብ ፡— ዘመኑ ፡ አልደረሰም ፥ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የሚሠራበት ፡ ዘመን ፡ አልደረሰም ፡ ይላል ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ። ፫ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ በነቢዩ ፡ በሐጌ ፡ ፬ እጅ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— በውኑ ፡ ይህ ፡ ቤት ፡ ፈርሶ ፡ ሳለ ፡ እናንተ ፡ ራሳችሁ ፡ በተሸለሙ ፡ ቤቶቻችሁ ፡ ለመኖር ፡ ጊዜው ፡ ነውን ? ፭ አሁንም ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ልባችሁን ፡ በመንገዳችሁ ፡ ፮ ላይ ፡ አድርጉ ። ብዙ ፡ ዘራችሁ ፥ ጥቂትም ፡ አገባችሁ ፤ በላችሁ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አልጠገባችሁም ፤ ጠጣችሁ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አልረካችሁም ፤ ለበሳችሁ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አልሞቃችሁም ፤ ደመወዝን ፡ የተቀበለ ፡ ሰው ፡ በቀዳዳ ፡ ከረጢት ፡ ያደርገው ፡ ዘንድ ፡ ደመወዙን ፡ ተቀበለ ።

፯ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ልባችሁን ፡ በመንገዳችሁ ፡ ላይ ፡ አድርጉ ። ፰ ወደ ፡ ተራራው ፡ ውጡ ፥ እንጨትንም ፡ አምጡ ፥ ቤቱንም ፡ ሥሩ ፤ እኔም ፡ በእርሱ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፥ እኔም ፡ እመሰገናለሁ ፥ ይላል ፡ ፱ እግዚአብሔር ። እናንተ ፡ ብዙ ፡ ነገርን ፡ ተስፋ ፡ አደረጋችሁ ፥ እነሆም ፥ ጥቂት ፡ ሆነ ፤ ወደ ፡ ቤትም ፡ በገባችሁት ፡ ጊዜ ፡ እፍ ፡ አልሁበት ። ይህ ፡ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። እናንተ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እየቤታችሁ ፡ እየሮጣችሁ ፡ የእኔ ፡ ቤት ፡ ፈርሶ ፡ ፲ ስለ ፡ ተቀመጠ ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ ሰማያት ፡ በላያችሁ ፡ ጠልን ፡ ከልክለዋል ፥ ምድሪቱም ፡ ፍሬ ፲፩ ዋን ፡ ከልክላለች ። እኔም ፡ በምድርና ፡ በተራሮች ፥ በእህልና ፡ በወይንም ፥ በዘይትና ፡ ምድርም ፡ በምታበቅለው ፡ ላይ ፥ በሰዎችና ፡ በእንስሶችም ፡ ላይ ፥ እጅም ፡ በሚደክምበት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ድርቅን ፡ ጠርቻለሁ ።

፲፪ የሰላትያልም ፡ ልጅ ፡ ዘሩባቤል ፥ ታላቁም ፡ ካህን ፡ የኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፥ የቀሩትም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ የአምላካቸውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ድምፅ ፡ የነቢዩንም ፡ የሐጌን ፡ ቃል ፥ አምላካቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ላከው ፡ ሁሉ ፡ ሰሙ ፤ ሕዝቡም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ፈሩ ። ፲፫ የእግዚአብሔርም ፡ መልእክተኛ ፡ ሐጌ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መልእክት ፡ ሕዝቡን ፡— እኔ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ነኝ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ። ፲፬ እግዚአብሔርም ፡ የይሁዳን ፡ አለቃ ፡ የሰላትያልን ፡ ልጅ ፡ የዘሩባቤልን ፡ መንፈስ ፥ የታላቁንም ፡ ካህን ፡ የኢዮሴዴቅን ፡ ልጅ ፡ የኢያሱን ፡ መንፈስ ፥ የቀሩትንም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ መንፈስ ፡ አስነሣ ፤ ፲፭ በንጉሡም ፡ በዳርዮስ ፡ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ በስድስተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በሀያ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ መጡ ፥ የአምላካቸውንም ፡ የሠራዊትን ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ሠሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በሀያ ፡ አንደኛው ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በነቢዩ ፡ በሐጌ ፡ እጅ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ፪ ለይሁዳ ፡ አለቃ ፡ ለሰላትያል ፡ ልጅ ፡ ለዘሩባቤል ፥ ለታላቁም ፡ ካህን ፡ ለኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ ለኢያሱ ፥ ለቀሩትም ፡ ሕዝብ ፡ እንዲህ ፡ ስትል ፡ ተናገር ፡— ፫ በቀድሞ ፡ ክብሩ ፡ ሳለ ፡ ይህን ፡ ቤት ፡ ያየ ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡ የቀረ ፡ ማን ፡ ነው ? ዛሬስ ፡ እንዴት ፡ ሆኖ ፡ አያችሁት ? በዓይናችሁ ፡ እንደ ፡ ምናምን ፡ አይደለምን ? ፬ አሁን ፡ ግን ፥ ዘሩባቤል ፡ ሆይ ፥ በርታ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ታላቁም ፡ ካህን ፡ የኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡ ሆይ ፥ በርታ ፥ እናንተም ፡ የአገሩ ፡ ሕዝብ ፡ ሆይ ፥ በርቱና ፡ ሥሩ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ እኔ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ነኝና ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ፭ መንፈሴም ፡ በመካከላችሁ ፡ ይኖራልና ፡ አትፍሩ ። ፮ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— ገና ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ በቅርብ ፡ ዘመን ፡ እኔ ፡ ሰማያትንና ፡ ምድርን ፡ ባሕርንና ፡ የብስንም ፡ አናውጣለሁ ፤ ፯ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ አናውጣለሁ ፥ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ የተመረጠውም ፡ ዕቃ ፡ ይመጣል ፤ ይህንም ፡ ቤት ፡ በክብር ፡ እሞላዋለሁ ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ፰ ብሩ ፡ የእኔ ፡ ነው ፥ ወርቁም ፡ የእኔ ፡ ነው ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ፱ ከፊተኛው ፡ ይልቅ ፡ የዚህ ፡ የሁለተኛው ፡ ቤት ፡ ክብር ፡ ይበልጣል ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ በዚህም ፡ ስፍራ ፡ ሰላምን ፡ እሰጣለሁ ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፲ በዳርዮስም ፡ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ በዘጠነኛው ፡ ወር ፡ በሀያ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በነቢዩ ፡ በሐጌ ፡ እጅ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ፲፩ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ካህናቱን ፡ ስለ ፡ ሕጉ ፡ ጠይቅ ፤ ፲፪ አንድ ፡ ሰው ፡ የተቀደሰ ፡ ሥጋ ፡ በልብሱ ፡ ዘርፍ ፡ ቢይዝ ፥ በዘርፉም ፡ እንጀራ ፡

ወይም፡ወጥ፥ወይም፡የወይን፡ጠጅ፥ወይም፡
ዘይት፥ ወይም፡ ማናቸውም፡ መብል፡ ቢነካ፡
ያ፡ የተነካው፡ በውኑ፡ ይቀደሳልን? ብለህ፡
ካህናቱን፡ ጠይቃቸው። ካህናቱም፡— አይሆ
፲፫ ንም፡ ብለው፡ መለሱ። ሐጌም፡— በሬሳ፡ የረ
ከሰ፡ሰው፡ ከእነዚህ፡ አንዱን፡ ቢነካ፡ ያ፡የተነ
ካው፡በውኑ፡ይረክሳልን? አለ። ካህናቱም፡—
፲፬ አዎን፡ ይረክሳል፡ ብለው፡ መለሱ። ሐጌም፡
መልሶ፡ እንዲህ፡ አለ፡— ይህ፡ ሕዝብና፡ ይህ፡
ወገን፡ በፊቴ፡ እንዲሁ፡ ነው፥ ይላል፡ እግዚ
አብሔር፤ የእጃቸውም፡ ሥራ፡ ሁሉ፡ እንዲሁ፡
ነው፤ በዚያም፡ ያቀረቡት፡ነገር፡ርኩስ፡ነው።
፲፭ አሁንም፡ ድንጋይ፡ በድንጋይ፡ ላይ፡ በእግዚ
አብሔር፡ መቅደስ፡ ሳይነበበር፥ ከዛሬ፡ ጀም
ራችሁ፡ ወዳለፈው፡ ዘመን፡ ልብ፡ አድርጉ።
፲፮ በዚያን፡ ዘመን፡ ሁሉ፡ ሰው፡ ሀያ፡ መስፈሪያ፡
ወዳለበት፡ ምርት፡ በመጣ፡ ጊዜ፥ የተገኘው፡
አሥር፡ መስፈሪያ፡ ብቻ፡ ነው፤ አምሳ፡ ማድ
ጋም፡ ይቀዳ፡ ዘንድ፡ ወደ፡ መጥመቂያው፡
በመጣ፡ ጊዜ፥ የተገኘው፡ ሀያ፡ ብቻ፡ ነው።
፲፯ በእጃችሁ፡ ሥራ፡ ሁሉ፡ ላይ፡ በዋግና፡ በአረ
ማሞ፡ በበረዶም፡ መታኋችሁ፤ እናንተ፡ ግን፡
ወደ፡ እኔ፡ አልተመለሳችሁም፥ይላል፡ እግዚአ
ብሔር። ከዛሬው፡ ከዘጠነኛው፡ ወር፡ ከሀያ፡
፲፰ አራተኛው፡ ቀን፡ ጀምራችሁ፡የሚመጣውን፡
ዘመን፡ ልብ፡ አድርጉ፤ የእግዚአብሔር፡ መቅ
ደስ፡ መሠረት፡ ከተተከለበት፡ ቀን፡ ጀምሮ፡
፲፱ ልብ፡ አድርጉ። ዘር፡ በጎተራ፡ ገና፡ ይኖራ
ልን? ወይንና፡ በለስ፡ ሮማንና፡ ወይራ፡ አላ
ፈሩም፤ ከዚህች፡ቀን፡ጀምሬ፡እባርካችኋለሁ።
፳ በወሩ፡ በሀያ፡ አራተኛው፡ ቀን፡ የእግዚአ
ብሔር፡ ቃል፡ ሁለተኛ፡ ወደ፡ ሐጌ፡ እንዲህ፡
፳፩ ሲል፡ መጣ፡— ለይሁዳ፡ አለቃ፡ ለዘሩባቤል፡
ተናገር፡ እንዲህም፡ በል፡— ሰማያትንና፡ምድ
፳፪ ርን፡ አናውጣለሁ፤ የመንግሥታትንም፡ዙፋን፡
እገለብጣለሁ፥ የአሕዛብንም፡ መንግሥታት፡
ኃይል፡ አጠፋለሁ፤ ሰረገሎችንና፡የሚቀመጡ
ባቸውንም፡ እገለብጣለሁ፤ ፈረሶችና፡ ፈረሰኞ
ቻቸውም፡ እያንዳንዳቸው፡ በወንድማቸው፡
፳፫ ሰይፍ፡ ይወድቃሉ። ባሪያዬ፡ የሰላትያል፡
ልጅ፡ ዘሩባቤል፡ ሆይ፥ በዚያ፡ ቀን፡ እወስድ
ሃለሁ፥ ይላል፡ የሠራዊት፡ ጌታ፡ እግዚአብ
ሔር፤ እኔ፡ መርጬሃለሁና፥ ይላል፡እግዚአብ
ሔር፥ እንደ፡ ቀለበት፡ ማተሚያ፡ አደርግሃ
ለሁ፥ ይላል፡የሠራዊት፡ጌታ፡እግዚአብሔር።

# ትንቢተ፡ ዘካርያስ።

## ምዕራፍ፡ ፩።

፩ በዳርዮስ፡ በሁለተኛው፡ ዓመት፡ በስምንተ
ኛው፡ ወር፡ የእግዚአብሔር፡ ቃል፡ ወደ፡ አዶ፡
ልጅ፡ ወደ፡ በራክዩ፡ ልጅ፡ ወደ፡ ነቢዩ፡ ወደ፡
፪ ዘካርያስ፡ እንዲህ፡ ሲል፡ መጣ፡— እግዚአብ
ሔር፡ በአባቶቻችሁ፡ ላይ፡ እጅግ፡ ተቈጥቶ፡
፫ ነበር። ስለዚህ፡ እንዲህ፡ በላቸው፡— የሠራ
ዊት፡ ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡—
ወደ፡ እኔ፡ ተመለሱ፥ ይላል፡ የሠራዊት፡ ጌታ፡
እግዚአብሔር፥ እኔም፡ ወደ፡ እናንተ፡ እመለ
ሳለሁ፥ ይላል፡ የሠራዊት፡ ጌታ፡ እግዚአብ
፬ ሔር። የቀደሙት፡ ነቢያት፡ ለአባቶቻችሁ፡
እንዲህ፡ ብለው፡ ሰብከዋል፡— የሠራዊት፡
ጌታ፡ እግዚአብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል፡— ከክፉ፡
መንገዳችሁና፡ ከክፉ፡ ሥራችሁ፡ ተመለሱ፤
እነርሱ፡ ግን፡ አልሰሙም፥ እኔንም፡ አላደመ
ጡም፤ እንደ፡ እነርሱ፡ አትሁኑ፥ ይላል፡ እግ
፭ ዚአብሔር። አባቶቻችሁ፡ ወዴት፡ ናቸው?
ነቢያትስ፡ ለዘላለም፡ በሕይወት፡ ይኖራሉን?
፮ ለባሪያዎቼስ፡ለነቢያት፡ያዘዝኋቸው፡ቃሎቼና፡
ሥርዓቴ፡ በአባቶቻችሁ፡ ላይ፡ አልደረሱምን?
እነርሱም፡ ተመልሰው፡— የሠራዊት፡ ጌታ፡
እግዚአብሔር፡ በመንገዳችንና፡ በሥራችን፡
መጠን፡ ያደርግብን፡ ዘንድ፡ እንዳሰበ፡ እንዲሁ፡
አድርጎብናል፡ አሉ።
፯ በዳርዮስ፡ በሁለተኛው፡ ዓመት፡ ሳባጥ፡
በሚባል፡ በአሥራ፡ አንደኛው፡ ወር፡ በሀያ፡
አራተኛው፡ ቀን፡ የእግዚአብሔር፡ ቃል፡ ወደ፡
አዶ፡ ልጅ፡ ወደ፡ በራክዩ፡ ልጅ፡ ወደ፡ ነቢዩ፡
፰ ወደ፡ ዘካርያስ፡ እንዲህ፡ ሲል፡ መጣ፡— እነ
ሆም፥ አንድ፡ ሰው፡ በመጋላ፡ ፈረስ፡ ተቀምጦ፡
በሌሊት፡ አየሁ፥ እርሱም፡ በሸለቆው፡ ውስጥ፡
ባሉ፡ በባርሰነት፡ ዛፎች፡ መካከል፡ ቆሞ፡ ነበር፤
በስተ፡ ኋላውም፡ መጋላና፡ ሐመር፡ አንባላ
፱ ይም፡ ፈረሶች፡ ነበሩ። እኔም፡— ጌታዬ፡ ሆይ፥
እነዚህ፡ ምንድር፡ ናቸው? አልሁ። ከእኔም፡
ጋር፡ ይነጋገር፡ የነበረው፡ መልአክ፡— እነዚህ፡
፲ ምን፡ እንደ፡ ሆኑ፡ አሳይሃለሁ፡ አለኝ። በባር
ሰነት፡ ዛፎች፡ መካከልም፡ ቆሞ፡ የነበረው፡
ሰው፡— እነዚህ፡ በምድር፡ ላይ፡ ይመላለሱ፡
ዘንድ፡ እግዚአብሔር፡ የላካቸው፡ ናቸው፡
፲፩ ብሎ፡ መለሰ። በባርሰነት፡ ዛፎች፡ መካከልም፡
ቆሞ፡ የነበረውን፡ የእግዚአብሔርን፡ መል
አክ፡— በምድር፡ ላይ፡ ተመላለስን፥ እነሆም፥
ምድር፡ ሁሉ፡ ዝም፡ ብላ፡ ዐርፋ፡ ተቀምጣ
ለች፡ ብለው፡ መለሱለት።
፲፪ የእግዚአብሔርም፡ መልአክ፡ መልሶ፡—
አቤቱ፥ የሠራዊት፡ ጌታ፡ ሆይ፥ እነዚህ፡ ሰባ፡
ዓመት፡ የተቈጣሃቸውን፡ ኢየሩሳሌምንና፡ የይ

ሁዳን ፡ ከተሞች ፡ የማትምራቸው ፡ እስከ ፡ መቼ ፡
፲፫ ነው ? አለ ። እግዚአብሔርም ፡ መልሶ ፡ ከእኔ ፡
ጋር ፡ ይነጋገር ፡ ለነበረው ፡ መልአክ ፡ በመልካ
፲፬ ምና ፡ በሚያጽናና ፡ ቃል ፡ ተናገረው ። ስለዚ
ህም ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ይነጋገር ፡ የነበረው ፡ መል
አክ ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡— ስበክ ፡ እንዲህም ፡
በል ፡— የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፡— እኔ ፡ በታላቅ ፡ ቅንዓት ፡ በኢየ
፲፭ ሩሳሌምና ፡ በጽዮን ፡ ቀንቻለሁ ። እኔ ፡ ጥቂት ፡
ብቻ ፡ ተቈጥቼ ፡ ሳለሁ ፡ እነርሱ ፡ ክፉትን ፡ ስላገ
ዙት ፥ በልተቸገሩት ፡ አሕዛብ ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡
፲፮ ተቈጥቻለሁ ። ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ እን
ዲህ ፡ ይላል ፡— ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በምሕረት ፡
ተመልሻለሁ ፤ ቤቴ ፡ ይሠራበታል ፤ በኢየሩሳ
ሌምም ፡ ላይ ፡ ገመድ ፡ ይዘረጋበታል ፥ ይልላ ፡
፲፯ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ደግሞም ፡ እን
ዲህ ፡ ስትል ፡ ስበክ ፡— የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ከተሞቼ ፡ ደግሞ ፡
በበጎ ፡ ነገር ፡ ይረከሉ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፡
ጽዮንን ፡ ያጽናናል ፥ ኢየሩሳሌምንም ፡ ደግሞ ፡
ይመርጣል ።

፲፰ ዓይኖቼንም ፡ እንሥቼ ፡ እነሆ ፥ አራት ፡ ቀን
፲፱ ዶች ፡ አየሁ ። ከእኔም ፡ ጋር ፡ ይነጋገር ፡ የነበረ
ውን ፡ መልአክ ፡— እነዚህ ፡ ምንድር ፡ ናቸው?
አልሁት ። እርሱም ፡— እነዚህ ፡ ይሁዳንና ፡ እስ
ራኤልን ፡ ኢየሩሳሌምንም ፡ የበተኑ ፡ ቀንዶች ፡
፳ ናቸው ፡ ብሎ ፡ መለሰልኝ ። እግዚአብሔርም ፡
፳፩ አራት ፡ ጠራቢዎች ፡ አሳየኝ ። እኔም ፡— እነ
ዚህ ፡ የመጡት ፡ ምን ፡ ሊሠሩ ፡ ነው ? አልሁ ።
እርሱም ፡— አንድ ፡ ሰው ፡ ራሱን ፡ እስከማያ
ነሣ ፡ ድረስ ፡ እነዚህ ፡ ቀንዶች ፡ ይሁዳን ፡ የበ
ተኑ ፡ ናቸው ፤ እነዚህ ፡ ግን ፡ ሊያስፈራሩአ
ቸው ፥ የይሁዳንም ፡ አገር ፡ ይበትኑ ፡ ዘንድ ፡
ቀንዳቸውን ፡ ያነሡትን ፡ የአሕዛብን ፡ ቀንዶች ፡
ሊጥሉ ፡ መጥተዋል ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ዓይኖቼንም ፡ አነሣሁ ፤ እነሆም ፥ በእጁ ፡
የመለኪያ ፡ ገመድ ፡ የያዘ ፡ አንድ ፡ ሰውን ፡ አየሁ ።
፪ እኔም ፡— አንተ ፡ ወዴት ፡ ትሄዳለህ ? አልሁ ።
እርሱም ፡— የኢየሩሳሌምን ፡ ወርድና ፡ ርዝ
መት ፡ስንት ፡ መሆኑን ፡ ሰፍሬ ፡ አይ ፡ ዘንድ ፡ እሄ
፫ ዳለሁ ፡ አለኝ ። እነሆም ፥ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ይነጋ
ገር ፡ የነበረው ፡ መልአክ ፡ ወጣ ፥ ሌላም ፡ መል
፬ አክ ፡ ሊገናኘው ፡ ወጣ ፥ እንዲህም ፡ አለው ፡—
ሩጥ ፥ ይህንም ፡ ጕልማሳ ፡ እንዲህ ፡ በለው ፡—
ኢየሩሳሌም ፡ በውስጥዋ ፡ ካሉት ፡ ሰዎችና ፡
እንስሶች ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ቅጥር ፡ እንደሌላ
፭ ቸው ፡ መንደሮች ፡ ሆና ፡ ትኖራለች ። እኔ ፡ በዙ
ሪያዋ ፡ የእሳት ፡ ቅጥር ፡ እሆንላታለሁ ፥ በውስ
ጥዋም ፡ ክብርን ፡ እሆናለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአ
ብሔር ።
፮ እናንተ ፡ ሆይ ፥ ከሰሜን ፡ ምድር ፡ ሽሹ ፥
ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ እንደ ፡ አራቱ ፡ የሰ
ማይ ፡ ነፋሳት ፡ በትኛችኋለሁና ፥ ይላል ፡ እግዚ
፯ አብሔር ። አንቺ ፡ ከባቢሎን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡
ጋር ፡ የምትኖሪ ፡ ጽዮን ፡ ሆይ ፥ ኰብልዪ ።
፰ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላልና ፡— ከክብሩ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ በዘበዙአ
ችሁ ፡ አሕዛብ ፡ ልኮኛል ፤ የሚነካችሁ ፡ የዓይ
፱ ኑን ፡ ብሌን ፡ የሚነካ ፡ ነውና ። እነሆ ፥ እጄን ፡
በላያቸው ፡ አወዛውዛለሁ ፥ ተገዝተው ፡ ለነበ
ሩት ፡ ብዝበዛ ፡ ይሆናሉ ፤ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ላከኝ ፡ ታውቃላችሁ ።
፲ የጽዮን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ እነሆ ፥ መጥቼ ፡ በመካ
ከልሽ ፡ እኖራለሁና ፡ ዘምሪ ፡ ደስም ፡ ይበልሽ ፥
፲፩ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ብዙ ፡
አሕዛብ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይጠጋሉ ፥ ሕዝ
ብም ፡ ይሆኑኛል ፤ በመካከልሽም ፡ እኖራለሁ ፥
የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡
፲፪ እንደ ፡ ላከኝ ፡ ታውቂአለሽ ። እግዚአብሔርም ፡
ይሁዳን ፡ እድል ፡ ፈንታው ፡ አድርጎ ፡ በተቀደ
ሰችው ፡ ምድር ፡ ይወርሰዋል ፥ ኢየሩሳሌም
፲፫ ንም ፡ ዳግመኛ ፡ ይመርጣል ። እግዚአብሔር ፡
ከተቀደሰ ፡ ማደሪያው ፡ ነቅቶአልና ፡ ሥጋ ፡
ለባሽ ፡ ሁሉ ፡ ሆይ ፥ በፊቱ ፡ ዝም ፡ በል ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ እርሱም ፡ ታላቁን ፡ ካህን ፡ ኢያሱን ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ ፊት ፡ ቆሞ ፡ አሳየኝ ፥
ሰይጣንም ፡ ይከስሰው ፡ ዘንድ ፡ በስተ ፡ ቀኙ ፡
፪ ቆሞ ፡ ነበር ። እግዚአብሔርም ፡ ሰይጣንን ፡—
ሰይጣን ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔር ፡ ይገሥጽህ ፤ ኢየ
ሩሳሌምን ፡ የመረጠ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይገሥ
ጽህ ፤ በውኑ ፡ ይህ ፡ ከእሳት ፡ የተነጠቀ ፡ ትን
፫ ታግ ፡ አይደለምን ? አለው ። ኢያሱም ፡ እድ
ፋም ፡ ልብስ ፡ ለብሶ ፡ በመልአኩ ፡ ፊት ፡ ቆሞ ፡
፬ ነበር ። እርሱም ፡ መልሶ ፡ በፊቱ ፡ የቆሙትን ፡—
እድፋሙን ፡ ልብስ ፡ ከእርሱ ፡ ላይ ፡ አውልቁ ፡
አላቸው ። እርሱንም ፡— እነሆ ፥ አበሳህን ፡ ከአ
ንተ ፡ አርቄአለሁ ፥ ጥሩ ፡ ልብስም ፡ አለብስሃ
፭ ለሁ ፡ አለው ። ደግሞ ፡— ንጹሕ ፡ ጥምጥም ፡
በራሱ ፡ ላይ ፡ አድርጉ ፡ አለ ። እነርሱም ፡ በራሱ ፡
ላይ ፡ ንጹሕ ፡ ጥምጥም ፡ አደረጉ ፥ ልብስንም ፡
አለበሱት ፤ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ በአ
ጠገቡ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ።
፮ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ በኢያሱ ፡ እን
፯ ዲህ ፡ ሲል ፡ አዳኘበት ፡— የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በመንገዴ ፡
ብትሄድ ፡ ትእዛዜንም ፡ ብትጠብቅ ፥ በቤቴ ፡
ላይ ፡ ትፈርዳለህ ፥ አደባባዮቼንም ፡ ትጠብቃ
ለህ ፥ በዚህም ፡ ከቆሙት ፡ ከእነዚህ ፡ ጋር ፡ መግ
፰ ባትን ፡ እሰጥሃለሁ ። ታላቁ ፡ ካህን ፡ ኢያሱ ፡
ሆይ ፥ ስማ ፤ በፊትህም ፡ የሚቀመጡት ፡ ባል
ንጀሮችህ ፡ ለምልክት ፡ የሚሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ናቸ
ውና ፡ ይስሙ ፤ እነሆ ፥ እኔ ፡ ባሪያዬን ፡ ቍጥ
፱ ቋጥ ፡ አወጣለሁ ። በኢያሱ ፡ ፊት ፡ ያኖርሁት ፡
ድንጋይ ፡ እነሆ ፡ አለ ፤ በአንዱ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡

ሰባት ፡ ዓይኖች ፡ አሉ ፤ እነሆ ፣ ቅርጹን ፡ እቀር
ጻለሁ ፣ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔር ፣ የዚያችንም ፡ ምድር ፡ በደል ፡ በአንድ ፡
፲ ቀን ፡ አስወግዳለሁ ። በዚያ ፡ ቀን ፣ ይላል ፡
የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፣ እያንዳንዱ ፡
ከወይኑና ፡ ከበለሱ ፡ በታች ፡ ሆኖ ፡ ባልንጀራ
ውን ፡ ይጠራል ።

ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ከእኔም ፡ ጋር ፡ ይነጋገር ፡ የነበረው ፡ መል
አክ ፡ ተመልሶ ፡ ከእንቅልፉ ፡ እንደሚነቃ ፡
፪ ሰው ፡ አነቃኝ ። እርሱም ፡— የምታየው ፡ ምን
ድር ፡ ነው ? አለኝ ። እኔም ፡— እነሆ ፣ ሁለንተ
ናው ፡ ወርቅ ፡ የሆነውን ፡ መቅረዝ ፡ አየሁ ፤
የዘይትም ፡ ማሰሮ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ነበረ ፣ ሰባ
ትም ፡ መብራቶች ፡ ነበሩበት ፤ በራሱም ፡ ላይ ፡
ለነበሩት ፡ መብራቶች ፡ ሰባት ፡ ቧምቧዎች ፡
፫ ነበሩአቸው ። ሁለት ፡ የወይራ ፡ ዛፎች ፣ አንዱ ፡
በማሰሮው ፡ በስተ ፡ ቀኝ ፡ አንዱም ፡ በስተ ፡
ግራው ፡ ሆነው ፣ በአጠገቡ ፡ ነበሩ ፡ አልሁ ።
፬ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ይነጋገር ፡ ለነበረውም ፡ መልአክ ፡
መልሼ ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፣ እነዚህ ፡ ምንድር ፡
፭ ናቸው ? አልሁት ። ከእኔ ፡ ጋር ፡ ይነጋገር ፡ የነ
በረውም ፡ መልአክ ፡ መልሶ ፡— እነዚህ ፡ ምን ፡
እንደ ፡ ሆኑ ፡ አታውቅምን ? አለኝ ። እኔም ፡—
፮ ጌታዬ ፡ ሆይ ፣ አላውቅም ፡ አልሁ ። መልሶም ፡—
ለዘሩባቤል ፡ የተባለው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡
ይህ ፡ ነው ፡— በመንፈሴ ፡ እንጂ ፡ በኃይልና ፡
በብርታት ፡ አይደለም ፣ ይላል ፡ የሠራዊት ፡
፯ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ታላቅ ፡ ተራራ ፡ ሆይ ፣
አንተ ፡ ምንድር ፡ ነህ ? በዘሩባቤል ፡ ፊት ፡ ደል
ዳላ ፡ ሜዳ ፡ ትሆናለህ ፤ ሰዎችም ፡— ሞገስ ፣
ሞገስ ፡ ይሁንለት ፡ ብለው ፡ እየጮኹ ፡ እርሱ ፡
መደምደሚያውን ፡ ድንጋይ ፡ ያወጣል ፡ ብሎ ፡
ተናገረኝ ።

፰ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፱ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የዘሩባቤል ፡ እጆች ፡
ይህን ፡ ቤት ፡ መሠረቱ ፣ የእርሱም ፡ እጆች ፡
ይፈጽሙታል ፤ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔርም ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ እንደ ፡ ላከኝ ፡ ታውቃ
፲ ላችሁ ። የጥቂቱን ፡ ነገር ፡ ቀን ፡ የናቀ ፡ ማን ፡
ነው ? እነዚህ ፡ ሰባቱ ፡ ደስ ፡ ብሎአቸው ፡ በዘ
ሩባቤል ፡ እጅ ፡ ቱንቢውን ፡ ያያሉ ፤ እነዚህም ፡
በምድር ፡ ሁሉ ፡ የሚዘዋወሩ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ዓይኖች ፡ ናቸው ።

፲፩ እኔም ፡ መልሼ ፡— በመቅረዙ ፡ በስተ ፡ ቀኝና ፡
በስተ ፡ ግራ ፡ ያሉ ፡ እነዚህ ፡ ሁለት ፡ የወይራ ፡
፲፪ ዛፎች ፡ ምንድር ፡ ናቸው ? አልሁት ። ሁለተ
ኛም ፡ መልሼ ፡— በሁለቱ ፡ የወርቅ ፡ ቧምቧ
ዎች ፡ አጠገብ ፡ ሆነው ፡ የወርቁን ፡ ዘይት ፡ የሚ
ያፈስሱ ፡ እነዚህ ፡ ሁለት ፡ የወይራ ፡ ቅርንጫፎች ፡
፲፫ ምንድር ፡ ናቸው ? አልሁት ። እርሱም ፡ መልሶ ፡—
እነዚህ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ አታውቅምን ?
አለኝ ። እኔም ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፣ አላውቅም ፡
፲፬ አልሁት ። እርሱም ፡— በምድር ፡ ሁሉ ፡ ጌታ ፡
አጠገብ ፡ የቆሙት ፡ ሁለቱ ፡ የተቀቡት ፡ እነ
ዚህ ፡ ናቸው ፡ አለኝ ።

ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ተመልሼም ፡ ዓይኖቼን ፡ አነሣሁ ፣ እነሆም ፣
አንድ ፡ በራሪ ፡ የመጽሐፍ ፡ ጥቅልል ፡ አየሁ ።
፪ እርሱም ፡— የምታየው ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለኝ ።
እኔም ፡— በራሪ ፡ የመጽሐፍ ፡ ጥቅልል ፡ አያለሁ ፤
ርዝመቱ ፡ ሀያ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ አሥር ፡ ክንድ ፡
፫ ነው ፡ አልሁ ። እንዲህም ፡ አለኝ ፡— ይህ ፡ በም
ድር ፡ ፊት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የሚወጣው ፡ እርግማን ፡
ነው ፤ የሚሰርቅ ፡ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ በዚህ ፡
በኩል ፡ እንደ ፡ ተጻፈው ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋል ፣ በሐ
ሰት ፡ የሚምልም ፡ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ በዚያ ፡
በኩል ፡ እንደ ፡ ተጻፈው ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋል ።
፬ እኔ ፡ አስወጣዋለሁ ፣ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፣ ወደሚሰርቀውም ፡ ቤት ፣ በሐ
ሰትም ፡ በስሜ ፡ ወደሚምለው ፡ ቤት ፡ ይገባል ፤
በቤቱም ፡ ውስጥ ፡ ይኖራል ፣ እርሱንም ፣ እን
ጨቱንና ፡ ድንጋዩን ፣ ይበላል ።

፭ ከእኔም ፡ ጋር ፡ ይነጋገር ፡ የነበረው ፡ መልአክ ፡
ወጥቶ ፡— ዓይኖችህን ፡ አንሣ ፣ ይህችም ፡ የም
ትወጣው ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ እይ ፡ አለኝ ።
፮ እኔም ፡— ምንድር ፡ ናት ? አልሁ ። እርሱም ፡—
ይህች ፡ የምትወጣው ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ ናት ፡
አለኝ ። ደግሞም ፡— በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያለ ፡
፯ በደላቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አለ ። እነሆም ፣ የእርሳ
ሱን ፡ መክሊት ፡ አነሡት ፤ እነሆም ፣ በኢፍ ፡
መስፈሪያው ፡ ውስጥ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ተቀ
፰ ምጣ ፡ ነበር ። እርሱም ፡— ይህች ፡ ክፋት ፡ ናት ፡
አለኝ ፤ በኢፍ ፡ መስፈሪያው ፡ ውስጥ ፡ ጣላት ፣
የእርሳሱንም ፡ ጠገራ ፡ በመስፈሪያ ፡ አፍ ፡ ላይ ፡
፱ ጣለ ። ዓይኖቼንም ፡ አንሥቼ ፡ አየሁ ፣ እነሆም ፣
ሁለት ፡ ሴቶች ፡ ወጡ ፣ ነፋስም ፡ በክንፎቻ
ቸው ፡ ነበረ ፤ ክንፎቻቸውም ፡ እንደ ፡ ሽመላ ፡
ክንፎች ፡ ነበሩ ፤ የኢፍ ፡ መስፈሪያውንም ፡
፲ በምድርና ፡ በሰማይ ፡ መካከል ፡ አነሡት ። ከእ
ኔም ፡ ጋር ፡ ይነጋገር ፡ የነበረውን ፡ መልአክ ፡—
እነዚህ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያውን ፡ ወዴት ፡ ይወ
፲፩ ስዱታል ? አልሁት ። እርሱም ፡— በሰናዖር ፡
ምድር ፡ ቤት ፡ ይሠሩለት ፡ ዘንድ ፡ ይወስዱታል ፤
በተዘጋጀም ፡ ጊዜ ፡ በዚያ ፡ በስፍራው ፡ ይኖ
ራል ፡ አለኝ ።

ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ተመልሼም ፡ ዓይኖቼን ፡ አነሣሁ ፣ እነሆም ፣
አራት ፡ ሰረገሎች ፡ ከሁለት ፡ ተራራ ፡ መካከል ፡
ሲወጡ ፡ አየሁ ፤ ተራሮቹም ፡ የናስ ፡ ተራሮች ፡
፪ ነበሩ ። በፊተኛው ፡ ሰረገላ ፡ መጋላ ፡ ፈረሶች ፣
በሁለተኛውም ፡ ሰረገላ ፡ ዱሪ ፡ ፈረሶች ፡ ነበሩ ፣
፫ በሦስተኛውም ፡ ሰረገላ ፡ አምባላይ ፡ ፈረሶች ፣
በአራተኛውም ፡ ሰረገላ ፡ ቅጥልጣል ፡ ፈረሶች ፡
፬ ነበሩ ። ከእኔ ፡ ጋር ፡ ይነጋገር ፡ ለነበረውም ፡

መልአክ ፡ መልሼ ፡— ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ እነዚህ ፡
፬ ምንድር ፡ ናቸው ? አልሁት ። መልአኩም ፡
መልሶ ፡— እነዚህ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡
ከቆሙበት ፡ ስፍራ ፡ የሚወጡ ፡ አራቱ ፡ የሰ
፮ ማይ ፡ ነፋሳት ፡ ናቸው ። ዳሪ ፡ ፈረሶች ፡ ያሉ
በት ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ይወጣል ፤ አምባላዮቹም ፡
ከእነርሱ ፡ በኋላ ፡ ይወጣሉ ፥ ቅዋልጣሎችም ፡
፯ ወደ ፡ ደቡብ ፡ ይወጣሉ ፡ አለኝ ። መጋላዎቹም ፡
ደግሞ ፡ ወጡ ፡ በምድርም ፡ ይመላለሱ ፡ ዘንድ ፡
ለመሄድ ፡ ይፈልጉ ፡ ነበር ፤ እርሱም ፡— ሂዱ ፥
በምድር ፡ ላይ ፡ ተመላለሱ ፡ አለ ። እነርሱም ፡
፰ በምድር ፡ ላይ ፡ ተመላለሱ ። ጮኾም ፡— እነሆ ፥
ወደ ፡ ሰሜን ፡ ምድር ፡ የሚወጡት ፡ እነርሱ ፡
መንፈሴን ፡ በሰሜን ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ አሳርፈ
ዋል ፡ ብሎ ፡ ተናገረኝ ።

፱ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እን
፲ ዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ከባቢሎን ፡ ከመጡት ፡
ምርኮኞች ፡ ከሔልዳይና ፡ ከጦብያ ፡ ከዮዳኤም ፡
ውሰድ ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ መጥተህ ፡ ወደ ፡ ሶፎ
ንያስ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢዮስያስ ፡ ቤት ፡ ግባ ።
፲፩ ብርንና ፡ ወርቅን ፡ ከእነርሱ ፡ ውሰድ ፥ አክሊ
ሎችንም ፡ ሥራ ፤ በታላቁም ፡ ካህን ፡ በኢዮሴ
ዴቅ ፡ ልጅ ፡ በኢያሱ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ድፋቸው ፥
፲፪ እንዲህም ፡ በለው ፡— የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ፥ ስሙ ፡
ቍጥቋጥ ፡ የሚባል ፡ ሰው ፡ በስፍራው ፡ ይበቅ
ላል ፥ የእግዚአብሔርንም ፡ መቅደስ ፡ ይሠራል ።
፲፫ እርሱ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መቅደስ ፡ ይሠራል ፥
ክብርንም ፡ ይሸከማል ፥ በዙፋኑም ፡ ላይ ፡ ተቀ
ምጦ ፡ ይነግሣል ፤ በዙፋኑም ፡ ላይ ፡ ካህን ፡ ይሆ
ናል ፥ የሰላምም ፡ ምክር ፡ በሁለቱ ፡ መካከል ፡
፲፬ ይሆናል ። አክሊሎችም ፡ ለሔሌምና ፡ ለጦብያ ፡
ለዮዳኤም ፡ ለሶፎንያስም ፡ ልጅ ፡ ለሔን ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ ውስጥ ፡ ለመታሰቢያ ፡
፲፭ ይሆናሉ ። በሩቅም ፡ ያሉት ፡ መጥተው ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ መቅደስ ፡ ይሠራሉ ፤ የሠራዊት ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ እንደ ፡
ላከኝ ፡ ታውቃላችሁ ። የአምላካችሁንም ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አጥብቃችሁ ፡ ብትሰሙ ፡
ይህ ፡ ይሆናል ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ በንጉሡም ፡ በዳርዮስ ፡ በአራተኛው ፡ ዓመት ፡
ካሴሉ ፡ በሚባል ፡ በዘጠነኛው ፡ ወር ፡ በአራተ
ኛው ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ዘካ
፪ ርያስ ፡ መጣ ። የቤቴልም ፡ ሰዎች ፡ ሳራሳርንና ፡
ሬጌሜሌክን ፡ ሰዎቻቸውንም ፡ በእግዚአብሔር ፡
፫ ፊት ፡ ይለምኑ ፡ ዘንድ ፥ ለሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ለእግ
ዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ካህናት ፡ ለነቢያትም ፡— በለ
ፉት ፡ ዓመታት ፡ እንዳደረግሁት ፡ በአምስተ
ኛው ፡ ወር ፡ መለየትና ፡ ማልቀስ ፡ ይገባኛልን ?
ብለው ፡ ይናገሩ ፡ ዘንድ ፡ ልከአቸው ፡ ነበር ።
፬ የሠራዊትም ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡
፭ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— ለምድሩ ፡
ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ለካህናትም ፡ እንዲህ ፡ ብለህ ፡
ተናገራቸው ፡— በዚህ ፡ በሰባው ፡ ዓመት ፡ በአ
ምስተኛውና ፡ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ በጾማችሁና ፡
ባለቀሳችሁ ፡ ጊዜ ፥ በውኑ ፡ ለእኔ ፡ ጾም ፡ ጾማ
፮ ችሁልኝ ? በምትበሉበትና ፡ በምትጠጡበትስ ፡
ጊዜ ፥ ለራሳችሁ ፡ የምትበሉና ፡ የምትጠጡ ፡
፯ አይደላችሁምን ? ኢየሩሳሌምና ፡ በዙሪያዋ ፡
ያሉ ፡ ከተሞች ፡ ገና ፡ ሰዎች ፡ በሉባቸው ፡ ጊዜ ፥
በምቾትም ፡ ተቀምጠው ፡ ሳሉ ፥ ደቡቡና ፡ ቈላ
ውም ፡ ሰዎች ፡ በሉባቸው ፡ ጊዜ ፥ እግዚአብ
ሔር ፡ በቀደሙት ፡ ነቢያት ፡ እጅ ፡ የተናገረ
ውን ፡ ቃል ፡ መስማት ፡ አይገባችሁምን ?

፰ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ዘካርያስ ፡
፱ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናግሮአል ፡— እው
ነተኛውን ፡ ፍርድ ፡ ፍረዱ ፤ ቸርነትንና ፡ ምሕ
ረትን ፡ ሁላችሁ ፡ ለወንድሞቻችሁ ፡ አድርጉ ፤
፲ መበለቲቱንና ፡ ድሀ ፡ አደጉን ፥ መጻተኛውንና ፡
ችግረኛውን ፡ አትበድሉ ፤ ከእናንተም ፡ ማንም ፡
በወንድሙ ፡ ላይ ፡ ክፋውን ፡ ነገር ፡ በልቡ ፡
፲፩ አያስብ ። እነርሱ ፡ ግን ፡ ደንደሳቸውን ፡ አዞሩ ፡
እንጂ ፡ መስማትን ፡ እምቢ ፡ አሉ ፤ እንዳይሰ
፲፪ ሙም ፡ ጆሮአቸውን ፡ አደነቈሩ ። የሠራዊትም ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በቀደሙት ፡ ነቢያት ፡
እጅ ፡ በመንፈሱ ፡ የላከውን ፡ ሕጉንና ፡ ቃሉን ፡
እንዳይሰሙ ፡ ልባቸውን ፡ እንደ ፡ አልማዝ ፡
አጠነከሩ ፤ ስለዚህ ፡ ከሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ከእግዚአ
፲፫ ብሔር ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡ ቍጣ ፡ መጣ ። እኔ ፡ በጠ
ራሁ ፡ ጊዜ ፡ እነርሱ ፡ እንዳልሰሙኝ ፥ እንዲሁ ፡
እነርሱ ፡ በሚጠሩበት ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ አልሰማም ፥
፲፬ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ ወደ
ማያውቁአቸውም ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ በዐውሎ ፡
ነፋስ ፡ በተንኋቸው ። እንዲሁ ፡ ከእነርሱ ፡ በኋላ ፡
ምድሪቱ ፡ በድማ ፡ ሆናለች ፥ የሚተላለፍባትና ፡
የሚመላለስባትም ፡ አልነበረም ፤ ያማረችው
ንም ፡ ምድር ፡ በድማ ፡ አደረጉአት ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ የሠራዊትም ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡
፪ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሠራዊት ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ስለ ፡
ጽዮን ፡ ታላቅ ፡ ቅንዓት ፡ ቀንቻለሁ ፥ በታላቅም ፡
፫ ቍጣ ፡ ስለ ፡ እርስዋ ፡ ቀንቻለሁ ። እግዚአብሔር ፡
እንዲህ ፡ ይላል ፡— ወደ ፡ ጽዮን ፡ ተመልሻለሁ ፥
በኢየሩሳሌምም ፡ መካከል ፡ እኖራለሁ ፤ ኢየሩ
ሳሌምም ፡ የእውነት ፡ ከተማ ፡ ትባላለች ፤ የሠ
ራዊትም ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ተራራ ፡ የተ
፬ ቀደሰ ፡ ተራራ ፡ ይባላል ። የሠራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ዳግመኛ ፡
ሽማግሌዎችና ፡ ባልቴቶች ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አደ
ባባይ ፡ ይቀመጣሉ ፤ ሰውም ፡ ሁሉ ፡ ከዕድሜው ፡
ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ምርኩዝ ፡ በእጁ ፡ ይይዛል ።
፭ የከተማይቱም ፡ አደባባዮች ፡ በእነዚያ ፡ በሚጫ
ወቱ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ይሞላሉ ።

፮ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በዚህ ፡ ወራት ፡ በዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ቅሬታ ፡ ዓይን ፡ ዘንድ ፡ ድንቅ ፡ ቢሆን ÷ በውኑ ፡ በእኔ ፡ ዓይን ፡ ዘንድ ፡ ደግሞ ፡ ድንቅ ፡ ይሆናልን ? ይላል ፡ ፯ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነሆ ÷ ሕዝቤን ፡ ከምሥራቅ ፡ ምድርና ፡ ከምዕራብ ፡ ፰ ምድር ፡ አድነዋለሁ ፤ አመጣቸዋለሁም ÷ በኢየሩሳሌምም ፡ ውስጥ ፡ ይኖራሉ ፤ እነርሱም ፡ ሕዝብ ፡ ይሆኑኛል ÷ እኔም ፡ በእውነትና ፡ በጽድቅ ፡ አምላክ ፡ እሆናቸዋለሁ ።

፱ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— መቅደሱ ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ከተመሠረተበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ ከነቢያት ፡ አፍ ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ በዚህ ፡ ዘመን ፡ የሰማችሁ ፡ እናንተ ፡ ሆይ ÷ እጃ ፲ ችሁን ፡ አበርቱ ። ከዚያ ፡ ወራት ፡ አስቀድሞ ፡ ለሰውና ፡ ለእንስሳ ፡ ዋጋ ፡ አልነበረምና ፤ እኔም ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ በወንድሙ ፡ ላይ ፡ አስነሥቼ ፡ ነበርና ፡ ከአስጨናቂው ፡ የተነሣ ፡ ለሚገባውና ፡ ፲፩ ለሚወጣው ፡ ሰላም ፡ አልነበረም ። አሁን ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ቀደመው ፡ ዘመን ፡ በዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ቅሬታ ፡ ላይ ፡ አልሆንም ÷ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ፲፪ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ነገር ፡ ግን ፡ ሰላምን ፡ እዘራለሁ ፤ ወይኑ ፡ ፍሬውን ፡ ይሰጣል ÷ ምድርም ፡ አዝመራዋን ፡ ታወጣለች ÷ ሰማያትም ፡ ጠላቸውን ፡ ይሰጣሉ ፤ ለዚህም ፡ ሕዝብ ፡ ቅሬታ ፡ ፲፫ ይህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አወርሳለሁ ። የይሁዳ ፡ ቤትና ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ÷ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ እርግማን ፡ እንደ ፡ ነበራችሁ ÷ እንዲሁ ፡ አድናችኋለሁ ÷ በረከትም ፡ ትሆናላችሁ ፤ አትፍሩ ÷ እጃችሁንም ፡ አበርቱ ።

፲፬ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— አባቶቻችሁ ፡ እጅግ ፡ ባስቈጡኝ ፡ ጊዜ ፡ ክፉ ፡ ለማድረግ ፡ እንዳሰብሁ ÷ እንዳል ተጸጸትሁም ÷ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚ ፲፭ አብሔር ÷ እንዲሁ ፡ ዳግመኛ ፡ ለኢየሩሳሌምና ፡ ለይሁዳ ፡ ቤት ፡ በዚህ ፡ ወራት ፡ በጎነትን ፡ ፲፮ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ አስቤአለሁ ፤ አትፍሩ ። የምትሠሩት ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ እያንዳንዳችሁ ፡ ከባልንጀራችሁ ፡ ጋር ፡ እውነትን ፡ ተነጋገሩ ፤ በበር ፡ አደባባያችሁም ፡ የእውነትንና ፡ የሰላምን ፡ ፲፯ ፍርድ ፡ ፍረዱ ፤ ሁላችሁም ፡ በባልንጀራችሁ ፡ ላይ ፡ ክፉን ፡ ነገር ፡ በልባችሁ ፡ አታስቡ ፤ የሐሰትንም ፡ መሐላ ፡ አትውደዱ ፤ ይህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እጠላለሁና ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

፲፰ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ፲፱ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡— የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— የአራተኛው ፡ ወር ፡ ጾም ፡ የአምስተኛውም ፡ የሰባተኛውም ፡ የአሥረኛውም ፡ ወር ፡ ጾም ፡ ለይሁዳ ፡ ቤት ፡ ደስታና ፡ ተድላ ፡ የሐሤትም ፡ በዓላት ፡ ይሆናል ፤ ስለዚህም ፡ እውነትንና ፡ ሰላምን ፡ ፳ ውደዱ ። የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በብዙ ፡ ከተሞች ፡ የሚቀመጡ ፡ አሕዛብ ፡ ገና ፡ ይመጣሉ ፤ በአንዲትም ፡ ፳፩ ከተማ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡— እግዚአብሔርን ፡ እንለምን ፡ ዘንድ ÷ የሠራዊትንም ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንፈልግ ፡ ዘንድ ፡ ኑ ፡ እንሂድ ፤ እኔም ፡ እሄዳለሁ ፡ እያሉ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ከተማ ፡ ፳፪ ይሄዳሉ ። ብዙ ፡ ወገኖችና ፡ ኃይለኞች ፡ አሕዛብ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሠራዊትን ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ÷ እግዚአብሔርንም ፡ ይለምኑ ፡ ዘንድ ፡ ይመጣሉ ። ፳፫ የሠራዊትም ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በዚያ ፡ ዘመን ፡ ከአሕዛብ ፡ቋንቋ ፡ ሁሉ ፡ አሥር ፡ ሰዎች ፡ የአንዱን ፡ አይሁዳዊ ፡ ሰው ፡ ልብስ ፡ ዘርፍ ፡ ይዘው ፡— እግዚአብሔር ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እንዳለ ፡ ሰምተናልና ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እንሂድ ፡ ይላሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ሸክም ፡ በሴድራክ ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ ነው ÷ በደማስቆም ፡ ላይ ፡ ያርፋል ፤ የእግዚአብሔር ፡ ዓይን ፡ ወደ ፡ ሰውና ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ነገድ ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤ ፪ ደግሞም ፡ በዳርቻዋ ፡ ባለችው ፡ በሐማት ፡ ላይ ÷ እጅግ ፡ ጠቢበኞች ፡ በሆኑ ፡ በጢሮስና ፡ ፫ በሲዶና ፡ ላይ ፡ ነው ። ጢሮስም ፡ ምሽግን ፡ ለራስዋ ፡ ሠርታለች ÷ ብሩንም ፡ እንደ ፡ አፈር ፡ ጥሩውንም ፡ ወርቅ ፡ እንደ ፡ መንገድ ፡ ጭቃ ፡ ፬ አከማችታለች ። እነሆ ÷ ጌታ ፡ ይገፍፋታል ÷ በባሕርም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ብርታትዋን ፡ ይመ ፭ ታል ፤ እርስዋም ፡ በእሳት ፡ ትበላለች ። አስቀሎና ፡ አይታ ፡ ትፈራለች ፤ ጋዛ ፡ ደግሞ ፡ አይታ ፡ እጅግ ፡ ትታመማለች ፤ አቃሮንም ፡ እንዲሁ ÷ ተስፋዋ ፡ ይቈረጣልና ፤ ንጉሡም ፡ ከጋዛ ፡ ይጠ ፮ ፋል ÷ በአስቀሎናም ፡ የሚቀመጥ ፡ አይገኝም ። የተደባለቀ ፡ ወገን ፡ በአዛጦን ፡ ይቀመጣል ÷ ፯ የፍልስጥኤማውያንንም ፡ ትዕቢት ፡ አጠፋለሁ ። ደሙንም ፡ ከአፉ ፡ ውስጥ ፡ ርኵሱንም ፡ ነገር ፡ ከጥርሱ ፡ መካከል ፡ አስወግዳለሁ ፤ እርሱም ፡ ደግሞ ፡ ለአምላካችን ፡ ቅሬታ ፡ ይሆናል ፤ በይሁዳም ፡ እንደ ፡ አለቃ ፡ ይሆናል ÷ አቃሮንም ፡ ፰ እንደ ፡ ኢያቡሳዊ ፡ ይሆናል ። እኔም ፡ ማንም ፡ እንዳይሄድና ፡ እንዳይመለስ ፡ እንደ ፡ ጠባቂ ፡ ጦር ፡ ሆኖ ፡ በቤቴ ፡ ዙሪያ ፡ ሰፈር ፡ አደርጋለሁ ፤ አሁንም ፡ በዓይኔ ፡ አይቻለሁና ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አስጨናቂ ፡ አያልፍባቸውም ።

፱ አንቺ ፡ የጽዮን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ እጅግ ፡ ደስ ፡ ይበልሽ ፤ አንቺ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ልጅ ፡ ሆይ ÷ እልል ፡ በዪ ፤ እነሆ ÷ ንጉሥሽ ፡ ጻድቅና ፡ አዳኝ ፡ ነው ፤ ትሑትም ፡ ሆኖ ፡ በአህያም ÷ በአህያይቱ ፡ ግልገል ፡ በውርንጫይቱ ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ፲ ወደ ፡ አንቺ ፡ ይመጣል ። ሰረገላውንም ፡ ከኤፍሬም ፡ ፈረሱንም ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ አጠፋለሁ ፤ የሰልፉም ፡ ቀስት ፡ ይሰበራል ÷ ለአሕዛብም ፡ ሰላምን ፡ ይናገራል ፤ ግዛቱም ፡ ከባሕር ፡ እስከ ፡

በሕር ፥ ከወንዙም ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ይሆናል ።

፲፩ ለአንቺም ፡ ደግሞ ፡ ስለ ፡ ቃል ፡ ኪዳንሽ ፡ ደም ፥ እስሮችሽን ፡ ውኃ ፡ ከሌለበት ፡ ጕድጓድ ፡ አውጥቻለሁ ። ፲፪ እናንተ ፡ በተስፋ ፡ የምትኖሩ ፡ እስሮች ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ ጽኑ ፡ አምባ ፡ ተመለሱ ፤ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ አድርጌ ፡ እንድመልስልሽ ፡ ዛሬ ፡ እነግርሻለሁ ። ፲፫ ይሁዳን ፡ ለእኔ ፡ ገትሬአለሁ ፤ ቀስቱን ፡ በኤፍሬም ፡ ሞልቼአለሁ ፤ ጽዮን ፡ ሆይ ፥ ልጆችሽን ፡ በግሪክ ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ አስነሣለሁ ፥ አንቺንም ፡ እንደ ፡ ኃያል ፡ ሰው ፡ ሰይፍ ፡ አደርግሻለሁ ። ፲፬ እግዚአብሔርም ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ይገለጣል ፥ ፍላጻውም ፡ እንደ ፡ መብረቅ ፡ ይወጣል ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ መለከትን ፡ ይነፋል ፥ በደቡብም ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ይሄዳል ። ፲፭ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይጠብቃቸዋል ፤ እነርሱም ፡ ይበሉአቸዋል ፥ የወንጭፉንም ፡ ድንጋዮች ፡ ይረግጣሉ ፤ እንደ ፡ ወይን ፡ ጠጅም ፡ ይጠጡአቸዋል ፥ እንደ ፡ ጥዋዎችም ፡ እንደ ፡ መሠዊያም ፡ ማዕዘኖች ፡ የተሞሉ ፡ ይሆናሉ ። ፲፮ በዚያም ፡ ቀን ፡ አምላካቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሕዝቡ ፡ መንጋ ፡ ያድናቸዋል ፤ እነርሱም ፡ ለአክሊል ፡ እንደሚሆኑ ፡ እንደ ፡ ክቡሩ ፡ ድንጋዮች ፡ ይሆናሉ ፥ በምድሩም ፡ ላይ ፡ ይብለጨለጫሉ ። ፲፯ በጎነቱ ፡ እንዴት ፡ ታላቅ ፡ ነው ! ውበቱስ ፡ እንዴት ፡ ታላቅ ፡ ነው ! እህል ፡ ጕበዛዝቱን ፥ ጕሽ ፡ ጠጅም ፡ ቈነጃጅቱን ፡ ያለመልማል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ በኋለኛው ፡ ዝናብ ፡ ጊዜ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዝናብን ፡ ለምኑ ፤ እግዚአብሔር ፡ መብረቅ ፡ ያደርጋል ፤ እርሱም ፡ የበልግ ፡ ዝናብን ፡ ለእያንዳንዱም ፡ በሜዳ ፡ ውስጥ ፡ ሣርን ፡ ይሰጣል ። ፪ ተራፊም ፡ ከንቱነትን ፡ ተናግረዋልና ፥ ምዋርተኞችም ፡ ውሸትን ፡ አይተዋልና ፤ ሕልምንም ፡ የሚያዩ ፡ በሐሰት ፡ ተናግረዋል ፥ በከንቱም ፡ ያጽናናሉ ፤ እረኛም ፡ የላቸውምና ፡ እንደ ፡ በጎች ፡ ተቅበዝብዘዋል ፡ ተጨንቀውማል ።

፫ ቍጣዬ ፡ በእረኞች ፡ ላይ ፡ ነድዶአል ፥ አውራ ፡ ፍየሎችንም ፡ እቀጣለሁ ፤ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ የይሁዳን ፡ ቤት ፡ መንጋውን ፡ ጐብኝቶአል ፥ በሰልፍም ፡ ውስጥ ፡ እንዳለ ፡ እንደ ፡ ክብሩ ፡ ፈረስ ፡ ያደርጋቸዋል ። ፬ ከእርሱ ፡ ዘንድ ፡ የማዕዘኑ ፡ ድንጋይ ፥ ከእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ችንካሩ ፥ ከእርሱም ፡ ዘንድ ፡ የሰልፉ ፡ ቀስት ፥ ከእርሱም ፡ ዘንድ ፡ አስገባሪው ፡ ሁሉ ፡ በአንድ ፡ ላይ ፡ ይመጣሉ ። ፭ በሰልፍም ፡ ጊዜ ፡ ጠላቶቻቸውን ፡ በመንገድ ፡ ጭቃ ፡ ውስጥ ፡ እንደሚረግጡ ፡ ኃያላን ፡ ይሆናሉ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ነውና ፡ ይዋጋሉ ፥ ፈረሰኞችም ፡ ያፍራሉ ። ፮ ወድጃቸዋለሁና ፡ የይሁዳን ፡ ቤት ፡ አበረታለሁ ፥ የዮሴፍንም ፡ ቤት ፡ አድናለሁ ፤ አደላድላቸዋለሁም ፤ እመልሳቸዋለሁ ፤ እኔም ፡ አምላካቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝና ፥ እኔም ፡ እሰማቸዋለሁና ፡ እንዳልጣልኋቸው ፡ ይሆናሉ ። ፯ የኤፍሬምም ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ኃያላን ፡ ይሆናሉ ፥ ልባቸውም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ እንደ ፡ ጠጣ ፡ ሰው ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤ ልጆቻቸውም ፡ አይተው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፥ ልባቸውም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሐሤት ፡ ያደርጋል ።

፰ ተቤዥቼአቸዋለሁና ፡ በፉጨት ፡ ጠርቼ ፡ እሰበስባቸዋለሁ ፤ ቀድሞም ፡ በዝተው ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ ይበዛሉ ። ፱ በአሕዛብም ፡ መካከል ፡ ብዘራቸው ፡ እንኳ ፡ በሩቅ ፡ አገር ፡ ሳሉ ፡ ያስቡኛል ፥ ከልጆቻቸውም ፡ ጋር ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉ ፥ ይመለሱማል ። ፲ ከግብጽም ፡ ምድር ፡ እመልሳቸዋለሁ ፥ ከአሦርም ፡ እሰበስባቸዋለሁ ፤ ወደ ፡ ገለዓድና ፡ ወደ ፡ ሊባኖስ ፡ ምድር ፡ አመጣቸዋለሁ ፥ የሚበቃም ፡ በታ ፡ አይገኝላቸውም ። ፲፩ እርሱም ፡ በጭንቅ ፡ ባሕር ፡ ያልፋል ፥ የባሕርንም ፡ ሞገድ ፡ ይመታል ፥ የወንዙም ፡ ጥልቅ ፡ ሁሉ ፡ ይደርቃል ፤ የአሦርም ፡ ትዕቢት ፡ ይዋረዳል ፥ የግብጽም ፡ በትረ ፡ መንግሥት ፡ ይርቃል ። ፲፪ በአምላካቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ አበረታቸዋለሁ ፥ በስሙም ፡ ይመካሉ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ሊባኖስ ፡ ሆይ ፥ ደጆችህን ፡ ክፈት ፥ እሳትም ፡ ዝግባዎችህን ፡ ትብላ ። ፪ የጥድ ፡ ዛፍ ፡ ሆይ ፥ ዝግባ ፡ ወድቆአልና ፥ ከበርቴዎችም ፡ ጠፍተዋልና ፡ ዋይ ፡ በል ፤ እናንተም ፡ የባሳን ፡ ዛፎች ፡ ሆይ ፥ ጽኑው ፡ ዱር ፡ ተቈርጦአልና ፡ ዋይ ፡ በሉ ። ፫ የእረኞች ፡ ክብር ፡ ተዋርዶአልና ፡ የዋይታቸው ፡ ድምፅ ፡ ተሰምቶአል ፤ የዮርዳኖስ ፡ ትዕቢት ፡ ተዋርዶአልና ፡ የአንበሶች ፡ ግሣት ፡ ድምፅ ፡ ተሰምቶአል ።

፬ አምላኬ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አለ ፡— ለእርድ ፡ የሚሆኑትን ፡ በጎች ፡ ጠብቅ ። ፭ የገዙአቸው ፡ ያርዱአቸዋል ፥ ራሳቸውንም ፡ እንደ ፡ በደለኞች ፡ አድርገው ፡ አይቈጥሩም ፤ የሸጡአቸውም ፡— ባለ ፡ ጠጋ ፡ ሆነናል ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ፡ ይላሉ ፤ እረኞቻቸውም ፡ አይራሩላቸውም ። ፮ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ለሚኖሩ ፡ አልራራም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ እነሆም ፥ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ በባልንጀራውና ፡ በንጉሡ ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣለሁ ፤ ምድሪቱንም ፡ ይመታሉ ፥ ከእጃቸውም ፡ አላድናቸውም ።

፯ እኔም ፡ ለእርድ ፡ የሚሆኑትን ፡ በጎች ፥ የመንጋውን ፡ ችግረኞች ፡ ጠበቅሁ ። ሁለት ፡ በትሮችንም ፡ ወሰድሁ ፤ የአንዲቱን ፡ ስም ፡ ውበት ፥ የሁለተኛይቱንም ፡ ስም ፡ ማሰሪያ ፡ ብዬ ፡ ጠራሁ ፤ መንጋውንም ፡ ጠበቅሁ ። ፰ በአንድ ፡ ወርም ፡ ሦስቱን ፡ እረኞች ፡ አጠፋሁ ፤ ነፍሴም ፡ ተሰቀቀቻቸው ፥ ነፍሳቸውም ፡ ደግሞ ፡ እኔን ፡ ጠላች ። ፱ እኔም ፡— እናንተን ፡ አልጠብቅም ፤ የሚሞ

ተው፡ ይሙት ፥ የሚጠፋውም፡ ይጥፋ ፤ የቀ
ረውም፡ እያንዳንዱ፡ የባልንጀራውን፡ ሥጋ፡
፲፤ ይብላ፡ አልሁ። እኔም፡ ከሕዝቦች፡ ሁሉ፡ ጋር፡
የገባሁትን፡ ቃል፡ ኪዳኔን፡ አፈርስ፡ ዘንድ፡
ውበት፡ የተባለችውን፡ በትሬን፡ ወስጄ፡ ቈረ
፲፩፤ ጥሁ። በዚያም፡ ቀን፡ ተሰበረች ፤ እንዲሁም፡
እኔን፡ የተመለከቱ፡ የመንጋው፡ ችግረኞች፡
የእግዚአብሔር፡ ቃል፡ እንደ፡ ነበረ፡ አወቁ።
፲፪፤ እኔም ፦ ደስ፡ ብሎአችሁ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ዋጋ
ዬን፡ ስጡኝ ፤ ያለዚያ፡ ግን፡ ተዉት፡ አልሁ።
እነርሱም፡ ለዋጋዬ፡ ሠላሳ፡ ብር፡ መዘኑ።
፲፫፤ እግዚአብሔርም ፦ የተስማሙበትን፡ የከበረ
ውን፡ ዋጋዬን፡ በግምጃ፡ ቤቱ፡ ውስጥ፡ አኑ
ረው፡ አለኝ። እኔም፡ ሠላሳውን፡ ብር፡ ወስጄ፡
በእግዚአብሔር፡ ቤት፡ ባለው፡ በግምጃ፡ ቤቱ፡
፲፬፤ ውስጥ፡ አኖርሁት። በይሁዳና፡ በእስራኤል፡
መካከል፡ ያለውንም፡ ወንድማማችነት፡ እሰ
ብር፡ ዘንድ፡ ማሰሪያ፡ የተባለችውን፡ ሁለተኛ
ይቱን፡ በትሬን፡ ቈረጥሁ።
፲፭፤ እግዚአብሔርም፡ እንዲህ፡ አለኝ ፦ዳግመ
፲፮፤ ኛም፡ የሰነፍን፡ እረኛ፡ ዕቃ፡ ውሰድ። እነሆ ፥
በአገሩ፡ ውስጥ፡ እረኛ፡ አስነሣለሁ ፤ እርሱም፡
የጠፋውን፡ አያስብም ፥ የባዘነውን፡ አይፈል
ግም ፥ የተሰበረውን፡ አይጠግንም ፤ የዳነው
ንም፡ አይቀልብም ፥ ነገር፡ ግን፡ የሰባውን፡
ሥጋ፡ ይበላል ፥ ሰኰናውንም፡ ይቀለጣጥማል።
፲፯፤ መንጋውን፡ ለሚተው፡ ለምናምንቴ፡ እረኛ፡
ወዮለት ! ሰይፍ፡ በክንዱና፡ በቀኝ፡ ዓይኑ፡
ላይ፡ ይሆናል ፤ ክንዱም፡ አጥብቃ፡ ትደርቃ
ለች ፥ ቀኝ፡ ዓይኑም፡ ፈጽማ፡ ትጨልማለች።

## ምዕራፍ፡ ፲፪።

፩፤ ስለ፡ እስራኤል፡ የተነገረ፡ የእግዚአብሔር፡
ቃል፡ ሸክም፡ ይህ፡ ነው።
ሰማያትን፡ የዘረጋ ፥ ምድርንም፡ የመሠረተ ፥
የሰውንም፡ መንፈስ፡ በውስጡ፡ የሠራ፡ እግዚ
፪፤ አብሔር፡ እንዲህ፡ ይላል ፦ እነሆ ፥ ኢየሩሳ
ሌምን፡ በዙሪያዋ፡ ላሉት፡ ለአሕዛብ፡ ሁሉ፡
የመንገድገድ፡ ዋንጫ፡ አደርጋታለሁ ፤ ደግ
ሞም፡ ኢየሩሳሌም፡ ስትከበብ፡ በይሁዳ፡ ላይ፡
፫፤ እንዲሁ፡ ይሆናል። በዚያም፡ ቀን፡ ኢየሩሳ
ሌምን፡ ለአሕዛብ፡ ሁሉ፡ ከባድ፡ ድንጋይ፡ አደ
ርጋታለሁ ፤ የሚሸከሙአት፡ ሁሉ፡ እጅግ፡ ይቈ
ስላሉ ፤ የምድርም፡ አሕዛብ፡ ሁሉ፡ በላይዋ፡
፬፤ ላይ፡ ይከማቻሉ። በዚያ፡ ቀን ፥ ይላል፡ እግ
ዚአብሔር ፥ ፈረስን፡ ሁሉ፡ በድንጋጤ ፥ ተቀ
ማጭንም፡ በእብድነት፡ እመታለሁ ፤ ዓይኖቼ
ንም፡ በይሁዳ፡ ላይ፡ እከፍታለሁ ፥ የአሕዛብ
ንም፡ ፈረሶች፡ ሁሉ፡ በዕውርነት፡ እመታለሁ።
፭፤ የይሁዳም፡ አለቆች፡ በልባቸው ፦ በኢየሩሳ
ሌም፡ ለሚኖሩ፡ በአምላካቸው፡ በሠራዊት፡
ጌታ፡ በእግዚአብሔር፡ ብርታት፡ አለ፡ ይላሉ።
፮፤ በዚያ፡ ቀን፡ የይሁዳን፡ አለቆች፡ በእንጨት፡
መካከል፡ እንዳለ፡ ትንታግ ፥ በነዶችም፡ መካ
ከል፡ እንዳለ፡ እንደ፡ ፋና፡ ነበልባል፡ አደርጋ
ቸዋለሁ ፤ በቀኝና፡ በግራ፡ በዙሪያ፡ ያሉትን፡
አሕዛብ፡ ሁሉ፡ ይበላሉ ፤ ከዚያም፡ ወዲያ፡
ኢየሩሳሌም፡ በስፍራዋ፡ በኢየሩሳሌም፡ ትኖ
፯፤ ራለች። እግዚአብሔርም፡ የዳዊት፡ ቤት፡
ክብርና፡ የኢየሩሳሌም፡ ሰዎች፡ ክብር፡ በይ
ሁዳ፡ ክብር፡ ላይ፡ እንዳይታበይ፡ የይሁዳን፡
፰፤ ድንኳኖች፡ አስቀድሞ፡ ያድናል። በዚያ፡
ቀን፡ እግዚአብሔር፡ በኢየሩሳሌም፡ ለሚኖ
ሩት፡ ይመክትላቸዋል ፤ በዚያም፡ ቀን፡ ከእነ
ርሱ፡ መካከል፡ ደካማው፡ እንደ፡ ዳዊት፡ ይሆ
ናል ፤ የዳዊትም፡ ቤት፡ በፊታቸው፡ እንደ፡
እግዚአብሔር፡ መልአክ፡ እንደ፡ አምላክ፡ ይሆ
፱፤ ናል። በዚያም፡ ቀን፡ በኢየሩሳሌም፡ ላይ፡
የሚመጡትን፡ አሕዛብ፡ ሁሉ፡ ለማጥፋት፡ እጋ
ደላለሁ።
፲፤ በዳዊትም፡ ቤት፡ ላይ ፥ በኢየሩሳሌምም፡
በሚኖሩት፡ ላይ ፥ የሞገስንና፡ የልመናን፡ መን
ፈስ፡ አፈስሳለሁ ፤ ወደ፡ እርሱም፡ ወደ፡ ወጉት፡
ይመለከታሉ ፤ ሰውም፡ ለአንድያ፡ ልጁ፡ እንደ
ሚያለቅስ፡ ያለቅሱለታል ፥ ሰውም፡ ለበኵር፡
ልጁ፡ እንደሚያዝን፡ በመራራ፡ ኀዘን፡ ያዝኑ
፲፩፤ ለታል። በዚያ፡ ቀን፡ በመጊዶን፡ ሜዳ፡ እንደ፡
ነበረው፡ እንደ፡ ሐዳድሪሞን፡ ልቅሶ፡ ታላቅ፡
፲፪፤ ልቅሶ፡ በኢየሩሳሌም፡ ይሆናል። ምድሪቱም፡
ታለቅሳለች ፤ እያንዳንዱ፡ ወገን፡ ለብቻው ፥
የዳዊት፡ ቤት፡ ወገን፡ ለብቻው ፥ ሴቶቻቸውም፡
ለብቻቸው ፤ የናታን፡ ቤት፡ ወገን፡ ለብቻው ፥
፲፫፤ ሴቶቻቸውም፡ ለብቻቸው ፤ የሌዊ፡ ቤት፡
ወገን፡ ለብቻው ፥ ሴቶቻቸውም፡ ለብቻቸው ፤
የሰሜኢ፡ ወገን፡ ለብቻው ፥ ሴቶቻቸውም፡
፲፬፤ ለብቻቸው ፤ የቀሩት፡ ወገኖች፡ ሁሉ፡ እያንዳ
ንዱ፡ ወገን፡ ለብቻው ፥ ሴቶቻቸውም፡ ለብቻ
ቸው፡ ያለቅሳሉ።

## ምዕራፍ፡ ፲፫።

፩፤ በዚያ፡ ቀን፡ ለዳዊት፡ ቤትና፡ በኢየሩሳ
ሌም፡ ለሚኖሩ፡ ከኀጢአትና፡ ከርኵሰት፡
፪፤ የሚያነጻ፡ ምንጭ፡ ይከፈታል። በዚያ፡ ቀን ፥
ይላል፡ የሠራዊት፡ ጌታ፡ እግዚአብሔር ፥ የጣ
ዖታትን፡ ስም፡ ከምድር፡ አጠፋለሁ ፥ ከዚያም፡
በኋላ፡ አይታሰቡም ፤ ደግሞም፡ ሐሰተኞችን፡
ነቢያትና፡ ርኩስ፡ መንፈስን፡ ከምድር፡ ላይ፡ አስ
፫፤ ወግዳለሁ። ማንም፡ ደግሞ፡ ትንቢት፡ ቢናገር፡
የወለዱት፡ አባቱና፡ እናቱ ፦ አንተ፡ በእግዚ
አብሔር፡ ስም፡ ሐሰትን፡ ተናግረሃልና፡ በሕይ
ወት፡ አትኖርም፡ ይሉታል ፤ ትንቢትንም፡ ሲና
ገር፡ የወለዱት፡ አባቱና፡ እናቱ፡ ይወጉታል።
፬፤ በዚያም፡ ቀን፡ ነቢያቱ፡ ሁሉ፡ ትንቢትን፡ ሲና
ገሩ፡ እያንዳንዱ፡ ስለ፡ ራእዩ፡ ያፍራል ፤ ያታ
ልሉም፡ ዘንድ፡ የማቅ፡ ልብስ፡ አይለብሱም።
፭፤ እርሱ፡ ግን ፦ ከታናሽነቴ፡ ጀምሮ፡ ባሪያ፡
ሆኜ፡ ነበርሁና፡ ገበሬ፡ ሰው፡ ነኝ፡ እንጂ፡
፮፤ ነቢይ፡ አይደለሁም፡ ይላል። ሰውም ፦ ይህ፡

በእጅህ፡መካከል፡ያለ፡ቍስል፡ምንድር፡ነው? ይለዋል ። እርሱም ፡— በወዳጆቼ ፡ ቤት፡ የቈሰልሁት ፡ ቍስል ፡ ነው ፡ ይላል ።

፯ ሰይፍ ፡ ሆይ ÷ ባልንጀራዬ ፡ በሆነው ፡ ሰው ፡ በእረኛዬ ፡ ላይ ፡ ንቃ ÷ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ እረኛውን ፡ ምታ ÷ በጎቹም ፡ ይበተናሉ ፤ እጄንም ፡ በታናናሾች ፡ ላይ ፡ እመልሳለሁ ። ፰ በምድርም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሁለት ፡ ክፍል ፡ ተቈርጠው ፡ ይሞታሉ ÷ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ሦስተኛውም ፡ ክፍል ፡ በእርስዋ ፡ ውስጥ ፡ ይቀራል ። ፱ ሦስተኛውንም ፡ ክፍል ፡ ወደ ፡ እሳት ፡ አገባለሁ ÷ ብርም ፡ እንደሚነጥር ፡ አነጥራቸዋለሁ ÷ ወርቅም ፡ እንደሚፈተን ፡ እፈትናቸዋለሁ ፤ እነርሱም ፡ ስሜን ፡ ይጠራሉ ÷ እኔም ፡ እሰማቸዋለሁ ፤ እኔም ፡— ይህ ፡ ሕዝቤ ፡ ነው ፡ እላለሁ ፤ እርሱም ፡— እግዚአብሔር ፡ አምላኬ ፡ ነው ፡ ይላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ እነሆ ÷ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ይመጣል ÷ ፪ ብዝበዛሽንም ፡ በውስጥሽ ፡ ይከፈላሉ ። አሕዛብንም ፡ ሁሉ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ ለሰልፍ ፡ እሰበስባለሁ ፤ ከተማይቱም ፡ ትያዛለች ÷ ቤቶችም ፡ ይበዘበዛሉ ÷ ሴቶችም ፡ ይነወራሉ ፤ የከተማይቱም ፡ እኩሌታ ፡ ለምርኮ ፡ ይወጣል ÷ የቀረው ፡ ሕዝብ ፡ ግን ፡ ከከተማ ፡ አይጠፋም ። ፫ እግዚአብሔርም ፡ ይወጣል ÷ በሰልፍም ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ተዋጋ ፡ ከእነዚያ ፡ አሕዛብ ፡ ጋር ፡ ይዋጋል ። ፬ በዚያም ፡ ቀን ፡ እግሮቹ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ትይዩ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ባለው ፡ በደብረ ፡ ዘይት ፡ ላይ ፡ ይቆማሉ ፤ ደብረ ፡ ዘይትም ፡ በመካከል ፡ ወደ ፡ ምሥራቅና ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ይሰነጠቃል ÷ እጅግም ፡ ታላቅ ፡ ሸለቆ ፡ ይሆናል ፤ የተራራውም ፡ እኩሌታ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ÷ እኩሌታውም ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ ይርቃል ። ፭ የተራሮችም ፡ ሸለቆ ፡ እስከ ፡ አጸል ፡ ይደርሳልና ፡ በተራሮች ፡ ሸለቆ ፡ ትሸሻላችሁ ፤ በይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ በዖዝያን ፡ ዘመን ፡ ከሆነው ፡ ከምድር ፡ መናወጥ ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ሸሻችሁ ፡ ትሸሻላችሁ ፤ አምላኬ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ከቅዱሳኑ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ይመጣል ። ፮ በዚያም ፡ ቀን ፡ በረዶና ፡ ውርጭ ፡ እንጂ ፡ ብርሃን ፡ አይሆንም ። ፯ አንድ ፡ ቀንም ፡ ይሆናል ÷ እርሱም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የታወቀ ፡ ይሆናል ፤ ቀንም ፡ አይሆንም ÷ ሌሊትም ፡ አይሆንም ፤ ሲመሽም ፡ ብርሃን ፡ ይሆናል ። ፰ በዚያም ፡ ቀን ፡ የሕይወት ፡ ውኃ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ይወጣል ፤ እኩሌታው ፡ ወደ ፡ ምሥራቁ ፡ ባሕር ÷ እኩሌታውም ፡ ወደ ፡ ምዕራቡ ፡ ባሕር ፡ ይሄዳል ፤ ይህ ፡ በበጋና ፡ በክረምት ፡ ይሆናል ።

፱ እግዚአብሔርም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ይነግሣል ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ አንድ ÷ ስሙም ፡ አንድ ፡ ይሆናል ። ፲ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ከጌባ ፡ጀምሮ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ ደቡብ ፡ በኩል ፡ እስካለችው ፡ እስከ ፡ ሬሞን ፡ ድረስ ፡ ተለውጣ ፡ እንደ ፡ ዓረባ ፡ ትሆናለች ፤ እርስዋም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ትላለች ÷ ከብንያምም ፡ በር ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ፊተኛው ፡ በር ፡ ስፍራ ፡ እስከ ፡ ማዕዘኑ ፡ በር ፡ ድረስ ÷ ከሐናንኤልም ፡ ግንብ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ንጉሡ ፡ መጥመቂያ ፡ ድረስ ፡ በስፍራዋ ፡ ትኖራለች ። ፲፩ ሰዎችም ፡ ይኖሩባታል ÷ ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ እርግማን ፡ አይሆንም ፤ ኢየሩሳሌምም ፡ ተዘልላ ፡ ትኖራለች ።

፲፪ እግዚአብሔርም ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ጋር ፡ የተዋጉትን ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ የሚቀሥፍበት ፡ ቸነፈር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ በእግራቸው ፡ ሲቆሙ ፡ ሥጋቸው ፡ ይበሰብሳል ÷ ዓይኖቻቸውም ፡ በዓይነ ፡ ስባቸው ፡ ውስጥ ፡ ይበሰብሳሉ ÷ ምላሳቸውም ፡ በአፋቸው ፡ ውስጥ ፡ ይበሰብሳል ። ፲፫ በዚያም ፡ ቀን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡ ሽብር ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ፤ እያንዳንዱም ፡ የባልንጀራውን ፡ እጅ ፡ ይይዛል ÷ እጁም ፡ በባልንጀራው ፡ እጅ ፡ ላይ ፡ ይነሣል ። ፲፬ ይሁዳም ፡ ደግሞ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ ይዋጋል ፤ በዙሪያም ፡ ያሉት ፡ የአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ሀብት ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ወርቅና ፡ ብር ፡ ልብስም ፡ ይሰበሰባል ። ፲፭ በፈረስና ፡ በበቅሎ ÷ በግመልና ፡ በአህያ ÷ በዚያም ፡ ሰፈር ፡ ባለ ፡ እንስሳ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የሆነ ፡ ቸነፈር ፡ እንደዚያ ፡ ያለ ፡ ቸነፈር ፡ ይሆናል ።

፲፮ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ ከመጡት ፡ ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ የቀሩት ፡ ሁሉ ፡ ለንጉሡ ፡ ለሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይሰግዱ ፡ ዘንድ ÷ የዳስ ፡ በዓልንም ፡ ያከብሩ ፡ ዘንድ ፡ በየዓመቱ ፡ ይወጣሉ ። ፲፯ ከምድርም ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ ለንጉሡ ፡ ለሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይሰግዱ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ለማይወጡ ፡ ለእነርሱ ፡ ዝናብ ፡ አይዘንብላቸውም ። ፲፰ የግብጽም ፡ ወገን ፡ ባይወጣ ፡ ወደዚያም ፡ ባይመጣ ÷ እግዚአብሔር ፡ የዳስ ፡ በዓልን ፡ ያከብሩ ፡ ዘንድ ፡ የማይወጡትን ፡ አሕዛብ ፡ የሚቀሥፍበት ፡ ቸነፈር ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ይሆናል ። ፲፱ የግብጽ ፡ ቅጣት ÷ የዳስ ፡ በዓልንም ፡ ያከብሩ ፡ ዘንድ ፡ የማይወጡት ፡ የአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ቅጣት ፡ እንደዚህ ፡ ይሆናል ። ፳ በዚያ ፡ ቀን ፡ በፈረሶች ፡ ሻኵራ ፡ ላይ ፡— ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ ፡ ተብሎ ፡ ይጻፋል ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ያሉ ፡ ምንቸቶች ፡ በመሠዊያው ፡ ፊት ፡ እንዳሉ ፡ ዳካዎች ፡ ይሆናሉ ። ፳፩ በኢየሩሳሌምና ፡ በይሁዳ ፡ ያሉ ፡ ምንቸቶችም ፡ ሁሉ ፡ ለሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሱ ፡ ይሆናሉ ፤ የሚሠዉትም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይመጣሉ ፡ ከእነዚያም ፡ ወስደው ፡ ይቀቅሉባቸዋል ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ በሠራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ከነዓናዊው ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲያ ፡ አይገኝም ።

* * *

# ት ን ቢ ተ ፡ ሚ ል ክ ያ ስ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ በሚልክያስ ፡ እጅ ፡ ለእስራኤል ፡ የሆነ ፡ የእ
ግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ሸክም ፡ ይህ ፡ ነው ።
፪፤ ወድጃችኋለሁ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ እና
ንተ ፡ ግን ፡— በምን ፡ ወደድኸን ? ብላችኋል ።
ዔሳው ፡ የያዕቆብ ፡ ወንድም ፡ አልነበረምን ?
ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ያዕቆብንም ፡ ወደድሁ ፥
፫፤ ዔሳውንም ፡ ጠላሁ ፤ ተራሮቹንም ፡ በረሃ ፡ አደ
ረግኋቸው ፥ ርስቱንም ፡ ለምድረ ፡ በዳ ፡ ቀበ
፬፤ ሮች ፡ አሳልፌ ፡ ሰጠኋቸው ። ኤዶምያስ ፡—
እኛ ፡ ፈርሰናል ፥ ነገር ፡ ግን ፡ የፈረሰውን ፡
መልሰን ፡ እንሠራለን ፡ ቢል ፥ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— እነርሱ ፡
ይሠራሉ ፥ እኔ ፡ ግን ፡ አፈርሳለሁ ፤ በሰዎችም ፡
ዘንድ ፡— የበደል ፡ ዳርቻና ፡ እግዚአብሔር ፡
፭፤ ለዘላለም ፡ የተቈጣው ፡ ሕዝብ ፡ ይባላል ። ዓይ
ኖቻችሁም ፡ ያያሉ ፥ እናንተም ፡— እግዚአብ
ሔር ፡ ከእስራኤል ፡ ዳርቻ ፡ ወዲያ ፡ ታላቅ ፡
ይሁን ፡ ትላላችሁ ።
፮፤ እናንተ ፡ ስሜን ፡ የምታቃልሉ ፡ ካህናት ፡
ሆይ ፥ ልጅ ፡ አባቱን ፥ ባሪያም ፡ ጌታውን ፡ ያከ
ብራል ፤ እኔስ ፡ አባት ፡ ከሆንሁ ፡ ክብሬ ፡ ወዴት ፡
አለ ? ጌታስ ፡ ከሆንሁ ፡ መፈራቴ ፡ ወዴት ፡ አለ ?
ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። እና
ንተም ፡— ስምህን ፡ ያቃለልን ፡ በምንድር ፡ ነው ?
፯፤ ብላችኋል ። በመሠዊያዬ ፡ ላይ ፡ ርኩስ ፡ እን
ጀራ ፡ ታቀርባላችሁ ። እናንተም ፡— ያረከስንህ ፡
በምንድር ፡ ነው ? ብላችኋል ። የእግዚአብሔር ፡
ገበታ ፡ የተናቀረ ፡ ነው ፡ በማለታችሁ ፡ ነው ።
፰፤ ዕውር ፡ መሥዋዕትንም ፡ ስታቀርቡ ፡ ይህ ፡ ክፉ ፡
አይደለምን ? አንካሳውንና ፡ የታመመውን ፡
ስታቀርቡ ፡ ይህ ፡ ክፉ ፡ አይደለምን ? ያንን ፡
ለአለቃህ ፡ አቅርብ ፤ በውኑ ፡ በአንተ ፡ ደስ ፡ ይለ
ዋልን ? ወይስ ፡ ፊትህን ፡ ይቀበላልን ? ይላል ፡
፱፤ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። አሁንም ፡
ጸጋን ፡ ይሰጠን ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለምኑ ፤
ይህ ፡ ከእጃችሁ ፡ የተሰጠ ፡ ሲሆን ፡ ከቶ ፡ ፊታ
ችሁን ፡ ይቀበላልን ? ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡
፲፤ እግዚአብሔር ። በመሠዊያዬ ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡
በከንቱ ፡ እንዳታቃጥሉ ፡ ከእናንተ ፡ ዘንድ ፡
ደጅ ፡ የሚዘጋ ፡ ሰው ፡ ምነው ፡ በተገኘ ! በእና
ንተ ፡ ደስ ፡ አይለኝም ፥ ቍርባንንም ፡ ከእጃ
ችሁ ፡ አልቀበልም ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡
፲፩፤ እግዚአብሔር ። ከፀሐይ ፡ መውጫ ፡ጀምሮ ፡
እስከ ፡ መግቢያዋ ፡ ድረስ ፡ ስሜ ፡ በአሕዛብ ፡
ዘንድ ፡ ታላቅ ፡ ይሆናልና ፤ በየስፍራውም ፡
ለስሜ ፡ ዕጣን ፡ ያጥናሉ ፥ ንጹሕም ፡ ቍርባን ፡
ያቀርባሉ ፤ ስሜ ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡
ይሆናልና ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአ
ብሔር ። እናንተ ፡ ግን ፡— የእግዚአብሔር ፡ ፲፪፤
ገበታ ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤ ፍሬውና ፡ መብሉም ፡ የተ
ናቀ ፡ ነው ፡ በማለታችሁ ፡ አስነቀፋችሁት ።
፲፫፤ እናንተ ፡— እነሆ ፥ ይህ ፡ ድካም ፡ ነው ፡ ብላ
ችሁ ፡ ጢቅ ፡ አላችሁበት ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ በቅሚያ ፡ የያዛችሁት
ንም ፡ አንካሳውንም ፡ የታመመውንም ፡ አቅር
ባችኋል ፤ እንዲሁ ፡ ቍርባንን ፡ ታመጣላችሁ ፤
በውኑ ፡ ከእጃችሁ ፡ ይህን ፡ ልቀበለውን ? ይላል ፡
፲፬፤ እግዚአብሔር ። እኔ ፡ ታላቅ ፡ ንጉሥ ፡ ነኝና ፥
ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥
ስሜም ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ የተፈራ ፡ ነውና ፡
በመንጋው ፡ ውስጥ ፡ ተባት ፡ እያለው ፡ ለጌታ ፡
ተስሎ ፡ ነውረኛውን ፡ የሚሠዋ ፡ ሸንጋይ ፡ ሰው ፡
ርጉም ፡ ይሁን ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፤ አሁንም ፡ እናንተ ፡ ካህናት ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡ ትእ
፪፤ ዛዝ ፡ ለእናንተ ፡ ነው ። ለስሜ ፡ ክብር ፡ ትሰጡ ፡
ዘንድ ፡ ባትሰሙ ፥ በልባችሁም ፡ ባታደርጉት ፥
ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥ እር
ግማን ፡ እሰድድባችኋለሁ ፥ በረከታችሁንም ፡
እረግማታለሁ ፤ አሁንም ፡ በልባችሁ ፡ አላደረጋ
፫፤ ችሁትምና ፡ እኔ ፡ ረግሜአታለሁ ። እነሆ ፥ ከን
ዳችሁን ፡ እገሥጻለሁ ፥ የመሥዋዕታችሁንም ፡
ፋንድያ ፡ በፊታችሁ ፡ ላይ ፡ እበትናለሁ ፤ ከእር
፬፤ ሱም ፡ ጋር ፡ በአንድነት ፡ ትወሰዳላችሁ ። ቃል ፡
ኪዳኔ ፡ ከሌዊ ፡ ጋር ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡ ትእ
ዛዝ ፡ እንደ ፡ ሰደድሁላችሁ ፡ ታውቃላችሁ ፥
፭፤ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ቃል ፡
ኪዳኔ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የሕይወትና ፡ የሰላም ፡
ቃል ፡ ኪዳን ፡ ነበረ ፤ ይፈራ ፡ ዘንድም ፡ እነር
ሱን ፡ ሰጠሁት ፤ እርሱም ፡ ፈራኝ ፥ ከስሜም ፡
፮፤ የተነሣ ፡ ደነገጠ ። የእውነት ፡ ሕግ ፡ በአፉ ፡
ውስጥ ፡ ነበረች ፥ በከንፈሩም ፡ ውስጥ ፡ በደል ፡
አልተገኘበትም ፤ ከእኔም ፡ ጋር ፡ በሰላምና ፡
በቅንነት ፡ ሄደ ፥ ብዙ ፡ ሰዎችንም ፡ ከኃጢአት ፡
፯፤ መለሰ ። ካህኑ ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ መልእክተኛ ፡ ነውና ፡ ከንፈሮቹ ፡ እውቀ
ትን ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ይገባቸዋል ፥ ሰዎችም ፡
ሕግን ፡ ከአፉ ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ፡ ይገባቸዋል ።
፰፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ከመንገዱ ፡ ፈቀቅ ፡ ብላችኋል ፤
በሕግም ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ አሰናክላችኋል ፤ የሌ
ዊንም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አስነውራችኋል ፥ ይላል ፡
፱፤ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ስለዚህ ፡ መን
ገዴን ፡ እንዳልጠበቃችሁ ፥ በሕግም ፡ ለሰው ፡
ፊት ፡ እንዳዳላችሁ ፡ መጠን ፥ እኔ ፡ ደግሞ ፡
በሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ የተናቃችሁና ፡ የተዋረ
ዳችሁ ፡ አድርጌአችኋለሁ ።
፲፤ ለሁላችን ፡ አንድ ፡ አባት ፡ ያለን ፡ አይደለምን ?

አንድ ፡ አምላክስ ፡ የፈጠረን ፡ አይደለምን ?
የአባቶቻችንን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ለማስነቀፍ ፡
እኛ ፡ እያንዳንዳችን ፡ ወንድማችንን ፡ ስለ ፡
፲፩ ምን ፡ አታለልን ? እግዚአብሔር ፡ የወደደውን ፡
መቅደስ ፡ ይሁዳ ፡ አርክሶአልና ፥ የእንግዳው
ንም ፡ አምላክ ፡ ልጅ ፡ ሚስት ፡ አድርጎ ፡ አግብ
ቶአልና ፡ ይሁዳ ፡ አታልሎአል ፥ በእስራኤ
ልና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ውስጥ ፡ ርኵሰት ፡ ተሠር
፲፪ ቶአል ። ይህን ፡ ከሚያደርግ ፡ ሰው ፥ እግዚአ
ብሔር ፡ የሚጠራውንና ፡ የሚመልሰውን ፡ ለሠ
ራዊትም ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቍርባን ፡
የሚያቀርበውን ፡ ከያዕቆብ ፡ ድንኳን ፡ ያጠፋል ።
፲፫ ይህንም ፡ ደግሞ ፡ አድርጋችኋል ፤ እግዚአብ
ሔር ፡ ቍርባኑን ፡ ዳግመኛ ፡ እንዳይመለከት ፥
ከእጃችሁም ፡ በደስታ ፡ እንዳይቀበለው ፡ መሠዊ
ያውን ፡ በእንባና ፡ በልቅሶ ፡ በኀዘንም ፡ ትከድና
፲፬ ላችሁ ። እናንተም ፦ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብላ
ችኋል ። ሚስትህ ፡ በልንጀራህና ፡ የቃል ፡ ኪዳ
ንህ ፡ ሚስት ፡ ሆና ፡ ሳለች ፡ እርስዋን ፡ አታልለ
ሃታልና ፡ እግዚአብሔር ፡ በአንተና ፡ በልጅነት ፡
ሚስትህ ፡ መካከል ፡ ምስክር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ነው ።
፲፭ እግዚአብሔር ፡ የሕይወትን ፡ መንፈስ ፡ አንድ ፡
አድርጎ ፡ ጠብቆልን ፡ የለምን ? እርሱም ፡ የሚ
ፈልገው ፡ ምንድር ፡ ነው ? ዘር ፡ አይደለምን ?
ስለዚህ ፡ መንፈሳችሁን ፡ ጠብቁ ፥ ማንም ፡ የል
፲፮ ጅነት ፡ ሚስቱን ፡ አያታልል ። መፋታትን ፡
እጠላለሁ ፥ ይላል ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግ
ዚአብሔር ፥ ልብሱንም ፡ በግፍ ፡ ሥራ ፡ የሚከ
ድነውን ፡ ሰው ፡ እጠላለሁ ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡
ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ ስለዚህ ፡ እንዳታታልሉ ፡
መንፈሳችሁን ፡ ጠብቁ ።

፲፯ እግዚአብሔርን ፡ በቃላችሁ ፡ አታክታች
ኋል ። እናንተም ፦ ያታከትነው ፡ በምንድር ፡
ነው ? ብላችኋል ። ክፉን ፡ የሚያደርግ ፡ ሁሉ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ መልካም ፡ ነው ፥ እር
ሱም ፡ በእነርሱ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤ ወይስ ፦
የፍርድ ፡ አምላክ ፡ ወዴት ፡ አለ ? በማለታችሁ ፡
ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ እነሆ ፥ መልእክተኛዬን ፡ እልካለሁ ፥ መንገ
ድንም ፡ በፊቴ ፡ ያስተካክላል ፤ እናንተም ፡ የም
ትፈልጉት ፡ ጌታ ፡ በድንገት ፡ ወደ ፡ መቅደሱ ፡
ይመጣል ፤ የምትወድዱትም ፡ የቃል ፡ ኪዳን ፡
መልእክተኛ ፥ እነሆ ፥ ይመጣል ፥ ይላል ፡ የሠራ
፪ ዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ነገር ፡ ግን ፡ እርሱ ፡
እንደ ፡ አንጥረኛ ፡ እሳትና ፡ እንደ ፡ አጣቢ ፡
ሳሙና ፡ ነውና ፡ የሚመጣበትን ፡ ቀን ፡ መታ
ገሥ ፡ የሚችል ፡ ማን ፡ ነው ? እርሱስ ፡ በተገ
፫ ለጠ ፡ ጊዜ ፡ የሚቆም ፡ ማን ፡ ነው ? እርሱም ፡
ብርን ፡ እንደሚያነጥርና ፡ እንደሚያጠራ ፡ ሰው ፡
ይቀመጣል ፥ የሌዊንም ፡ ልጆች ፤ ያጠራል ፥
እንደ ፡ ወርቅና ፡ እንደ ፡ ብርም ፡ ያነጥራቸዋል ፤
እነርሱም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በጽድቅ ፡ ቍርባ
ንን ፡ የሚያቀርቡ ፡ ይሆናሉ ። ፬ እግዚአብሔ
ርም ፡ እንደ ፡ ዱሮው ፡ ዘመንና ፡ እንደ ፡ ቀደ
ሙት ፡ ዓመታት ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡
ቍርባን ፡ ደስ ፡ ይለዋል ። ፭ ለፍርድ ፡ ወደ ፡ እና
ንተ ፡ እቀርባለሁ ፤ በመተተኞችና ፡ በአመንዝ
ሮች ፥ በሐሰትም ፡ በሚምሉ ፥ የምንደኛውን ፡
ደመወዝ ፡ በሚከለክሉ ፥ መበለቲቱንና ፡ ድሀ ፡
አደጉን ፡ በሚያስጨንቁ ፥ የመጻተኛውንም ፡
ፍርድ ፡ በሚያጣምሙ ፥ እኔንም ፡ በማይፈሩ ፡
ላይ ፡ ፈጣን ፡ ምስክር ፡ እሆንባቸዋለሁ ፥ ይላል ፡
የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ፮ እኔ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ አልለወጥም ፤ እናንተ ፡ የያዕቆብ ፡
ልጆች ፡ ሆይ ፥ ስለዚህ ፡ የጠፋችሁ ፡ አይደላ
ችሁም ።

፯ ከአባቶቻችሁ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ ከሥርዓቴ ፡
ፈቀቅ ፡ ብላችኋል ፥ እርስዋንም ፡ አልጠበቃች
ሁም ። ወደ ፡ እኔ ፡ ተመለሱ ፥ እኔም ፡ ወደ ፡ እና
ንተ ፡ እመለሳለሁ ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ። እናንተ ፡ ግን ፦ የምንመለ
ሰው ፡ በምንድር ፡ ነው ? ብላችኋል ። ፰ ሰው ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ ይሰርቃልን ? እናንተ ፡ ግን ፡ እኔን ፡
ሰርቃችኋል ። እናንተም ፦ የሰረቅንህ ፡ በም
ንድር ፡ ነው ? ብላችኋል ። በአሥራትና ፡ በበኵ
ራት ፡ ነው ። ፱ እናንተ ፥ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፥
እኔን ፡ ሰርቃችኋልና ፡ በእርግማን ፡ ርጉሞች ፡
ናችሁ ። ፲ በቤቴ ፡ ውስጥ ፡ መብል ፡ እንዲሆን ፡
አሥራቱን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ጎተራ ፡ አግቡ ፤ የሰማ
ይንም ፡ መስኮት ፡ ባልከፍትላችሁ ፥ በረከት
ንም ፡ አትረፍርፌ ፡ ባላፈስስላችሁ ፡ በዚህ ፡
ፈትኑኝ ፥ ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔር ። ፲፩ ስለ ፡ እናንተ ፡ ነቀዙን ፡ እገሥጻለሁ ፥
የምድራችሁንም ፡ ፍሬ ፡ አያጠፋም ፤ በእርሻች
ሁም ፡ ያለው ፡ ወይን ፡ ፍሬውን ፡ አያረግፍም ፥
ይላል ፡ የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። ፲፪ የተ
ድላ ፡ ምድር ፡ ትሆናላችሁና ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡
ብፁዓን ፡ ብለው ፡ ይጠሩአችኋል ፥ ይላል ፡ የሠ
ራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

፲፫ ቃላችሁ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ድፍረት ፡ ሆኖአል ፥
ይላል ፡ እግዚአብሔር ። እናንተ ፡ ግን ፦ በአ
ንተ ፡ ላይ ፡ ደፍረን ፡ የተናገርነው ፡ በምንድር ፡
ነው ? ብላችኋል ። ፲፬ እናንተም ፦ እግዚአብሔ
ርን ፡ ማገልገል ፡ ከንቱ ፡ ነው ፤ ትእዛዙንስ ፡ በመ
ጠበቅ ፥ በሠራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ኀዘንተኞች ፡ ሆነን ፡ በመሄድ ፡ ምን ፡ ይረ
ባናል ? ፲፭ አሁንም ፡ የሚታበዩትን ፡ ሰዎች ፡ ብፁ
ዓን ፡ ብለን ፡ እንጠራቸዋለን ፤ ክፉንም ፡ የሚ
ሠሩ ፡ ጸንተዋል ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ይፈታተ
ናሉ ፥ ያመልጣሉም ፡ ብላችኋል ።

፲፮ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡
እርስ ፡ በእርሳቸው ፡ ተነጋገሩ ፤ እግዚአብሔ
ርም ፡ አደመጠ ፥ ሰማም ፥ እግዚአብሔርንም ፡
ለሚፈሩ ፡ ስሙንም ፡ ለሚያስቡ ፡ የመታሰቢያ ፡
መጽሐፍ ፡ በፊቱ ፡ ተጻፈ ። ፲፯ እኔ ፡ በምሠራበት ፡
ቀን ፡ እነርሱ ፡ የእኔ ፡ ገንዘብ ፡ ይሆናሉ ፥ ይላል ፡

የሠራዊት፡ጌታ፡እግዚአብሔር፤ሰውም፡የሚያገለግለውን፡ልጁን፡እንደሚምር÷እንዲሁ፡
፲፰፤ እምራቸዋለሁ። ተመልሳችሁም፡በጻድቁና፡በኃጢአተኛው፡ መካከል÷ለእግዚአብሔር፡በሚገዛውና፡በማይገዛው፡ መካከል፡ ትለያላችሁ።

## ምዕራፍ፡፬።

፩፤ እነሆ÷እንደ፡ምድጃ፡እሳት፡የሚነድድ፡ቀን፡ይመጣል፤ትዕቢተኞችና፡ኃጢአትን፡የሚሠሩ፡ ሁሉ፡ ገለባ፡ ይሆናሉ፤የሚመጣውም፡ ቀን፡ ያቃጥላቸዋል÷ሥርንና፡ ቅርንጫፍንም፡ አይተውላቸውም÷ይላል፡ የሠ
፪፤ ራዊት፡ ጌታ፡ እግዚአብሔር። ነገር፡ ግን፡ ስሜን፡ ለምትፈሩት፡ ለእናንተ፡ የጽድቅ፡ ፀሐይ፡ ትወጣላችኋለች÷ፈውስም፡ በክንፎችዋ፡ውስጥ፡ይሆናል፤ እናንተም፡ትወጣላችሁ÷እንደ፡ሰባም፡እምቦሳ፡ትፈነጫላችሁ።
፫፤ በምሠራበት፡ቀን፡ በደለኞች፡ ከእግራችሁ፡ጫማ፡በታች፡ አመድ፡ይሆናሉና፡እናንተ፡ትረግጡአቸዋላችሁ÷ይላል፡የሠራዊት፡ጌታ፡እግዚአብሔር።

፬፤ ለእስራኤል፡ሁሉ፡ ሥርዓትንና፡ ፍርድን፡ አድርጌ፡ በኮሬብ፡ ያዘዝሁትን፡ የባሪያዬን፡የሙሴን፡ሕግ፡አስቡ። እነሆ÷ታላቁና፡የሚ
፭፤ ያስፈራው፡የእግዚአብሔር፡ ቀን፡ሳይመጣ፡ነቢዩን፡ ኤልያስን፡ እልክላችኋለሁ። መጥ
፮፤ ቼም፡ ምድርን፡ በእርግማን፡ እንዳልመታ፡ እርሱ፡የአባቶችን፡ልብ፡ወደ፡ልጆች÷የልጆችንም፡ልብ፡ወደ፡አባቶች፡ይመልሳል።

## የጌታችንና ፡ የመድኃኒታችን ፡

## የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡

# አዲስ ፡ ኪዳን ።

በግርማዊ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዘኢትዮጵያ ፡
መልካም ፡ ፈቃድና ፡ ትእዛዝ ፡
ታርሞና ፡ ተዘጋጅቶ ፡ ታተመ ።

# መግለጫ ።

ብሉይ ፡ ኪዳንን ፡ ከአዲስ ፡ ኪዳን ፡ ጋር ፡ ለማስማማት ፡ አዲሱንም ፡ አርስ ፡ በርሱ ፡ ለመመርመር ፡ ከታች ፡ በገጹ ፡ ኅዳግ ፡ ተመልከት ። አንድ ፡ መጽሐፍ ፡ በምዕራፎች ፡ ይከፈላል ፤ እያንዳንዱም ፡ ምዕራፍ ፡ በቍጥሮች ፡ ይከፈላል ፤ እንደ ፡ እነዚህ ፡ ያሉትም ፡ ቍጥሮች ፡ የኃይለ ፡ ቃል ፡ ቍጥሮች ፡ ይባላሉ ።

በስተ ፡ ግራ ፡ ለብቻው ፡ የሚገኘው ፡ ቍጥር ፡ ከበላዩ ፡ ያለው ፡ የምዕራፍ ፡ ቍጥር ፡ ነው ።

በምዕራፍ ፡ ውስጥ ፡ ለሚገኘው ፡ ለእያንዳንዱ ፡ የኃይለ ፡ ቃል ፡ ቍጥር ፡ የተጠቀሰለት ፡ ሁሉ ፡ ሲጨረስ ፡ አራት ፡ ነጥብ ፡ ይገኛል ። ከአራት ፡ ነጥብ ፡ በኋላ ፡ የምዕራፉ ፡ ሌላ ፡ የኃይለ ፡ ቃል ፡ ቍጥር ፡ ይገኛል ፤ ከዚህም ፡ ቍጥር ፡ በኋላ ፡ ይህ ፡ ዓቢይ ፡ ሠረዝ "፤" ይታያል ።

ይህ ፡ ንኡስ ፡ ሠረዝ "፥" የምዕራፉን ፡ ቍጥርና ፡ የኃይለ ፡ ቃሉን ፡ ቍጥር ፡ ሁልጊዜ ፡ ይከፍላል ። ለምሳሌ ፤ "፪፥፮ ፤" ማለት ፡ ሁለተኛ ፡ ምዕራፍና ፡ ስድስተኛ ፡ የኃይለ ፡ ቃል ፡ ቍጥር ፡ ማለት ፡ ነው ።

ለአንድ ፡ የኃይለ ፡ ቃል ፡ ቍጥር ፡ ብዙ ፡ ጥቅስ ፡ ሲኖረው ፡ ከእያንዳንዱ ፡ ጥቅስ ፡ በኋላ ፡ ይህ "፤" ይገኛል ፡ ከዚህም ፡ ምልክት ፡ በኋላ ፡ ጥቅስ ፡ የተጠቀሰበት ፡ የመጽሐፉ ፡ ስም ፡ በአጭር ፡ ተጽፎአል ። ለምሳሌ ፤ "፪ ፤ ዘፍጥ." ማለት ፡ በምዕራፉ ፡ ውስጥ ፡ ለሁለተኛው ፡ ቍጥር ፡ የተጠቀሰው ፡ የመጽሐፉ ፡ ስም ፡ ኦሪት ፡ ዘፍጥረት ፡ መሆኑን ፡ የሚያመለክት ነው ።

ከዚህ ፡ ምልክት "፤" በኋላ ፡ የመጽሐፍ ፡ ስም ፡ ባይገኝ ፡ ከአንድ ፡ መጽሐፍ ፡ ሁለት ፡ ጥቅስ ፡ እንደ ፡ ተጠቀሰ ፡ ይታወቃል ። ለምሳሌ ፤ "ዘፍጥ ፡ ፪፥፬ ፤ ፫፥፳ ።" ማለት ፡ ሁለቱም ፡ ጥቅስ ፡ ከኦሪት ፡ ዘፍጥረት ፡ ተጠቀሰ ፡ ማለት ፡ ነው ።

በመጽሐፍ ፡ ስም ፡ ፈንታ ፡ "ቍ" የሚል ፡ ሲገኝ ፡ "ቍ" ማለት ፡ ከላይ ፡ በተጻፈው ፡ በዚያው ፡ ምዕራፍ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ የኃይለ ፡ ቃል ፡ ቍጥር ፡ ማለት ፡ ነው ። "ም" ቢገኝ ፡ "ም" ማለት ፡ የዚያው ፡ መጽሐፍ ፡ ሌላ ፡ ምዕራፍ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ምናልባት ፡ ከንኡስ ፡ ሠረዝ "፥" በኋላ ፡ ሁለት ፡ ቍጥር ፡ ይገኝ ፡ ይሆናል ። በሁለቱ ፡ መካከል ፡ ሁለት ፡ ነጥብ ፡ የተገኘ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እያንዳንዱ ፡ ቍጥር ፡ ለብቻ ፡ ነው ፡ ማለት ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ በሁለቱ ፡ መካከል ፡ ይህ ፡ ምልክት ፡ "—" ሲገኝ ፡ ከፊተኛው ፡ ቍጥር ፡ እንሥቶ ፡ እስከ ፡ ተከታዩ ፡ ቍጥር ፡ ድረስ ፡ ያሉትን ፡ ቍጥሮች ፡ ሁሉ ፡ ተመልከት ፡ ማለት ፡ ነው ። ለምሳሌ ፤ "፩፡፬" ማለት ፡ አንደኛና ፡ አራተኛ ፡ ቍጥሮችን ፡ ብቻ ፡ ተመልከት ፡ ማለት ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ "፩—፬" ማለት ፡ ከአንደኛ ፡ እስከ ፡ አራተኛ ፡ ቍጥሮች ፡ ያሉትን ፡ ሁሉ ፡ ተመልከት ፡ ማለት ፡ ነው ።

ከዚህ ፡ በሚከተለው ፡ ገጽ ፡ የተጻፉት ፡ የቃል ፡ ማሳጠሪያ ፡ ቃሎች ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ የሚገኙ ፡ ናቸው ።

Eg. and.

: for vss, ፤ for chapters

# የአዲስ፡ኪዳን፡መጻሕፍት ።

# የጌታችን፡የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ወንጌል፡
# ቅዱስ፡ማቴዎስ፡እንደ፡ጻፈው።

## ምዕራፍ፡፩።

፩ የዳዊት፡ልጅ፡የአብርሃም፡ልጅ፡የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ትውልድ፡መጽሐፍ።

፪ አብርሃም፡ይስሐቅን፡ወለደ፤ ይስሐቅም፡ያዕቆብን፡ወለደ፤ ያዕቆብም፡ይሁዳንና፡ወንድሞቹን፡ወለደ፤ ፫ ይሁዳም፡ከትዕማር፡ፋሬስንና፡ዛራን፡ወለደ፤ ፋሬስም፡ኤስሮምን፡ወለደ፤ ፬ ኤስሮምም፡አራምን፡ወለደ፤ አራምም፡አሚናዳብን፡ወለደ፤ አሚናዳብም፡ነአሶንን፡ወለደ፤ ነአሶንም፡ሰልሞንን፡ወለደ፤ ፭ ሰልሞንም፡ከራኬብ፡ቦኤዝን፡ወለደ፤ ቦኤዝም፡ከሩት፡ኢዮቤድን፡ወለደ፤ ኢዮቤድም፡እሴይን፡ወለደ፤ ፮ እሴይም፡ንጉሥ፡ዳዊትን፡ወለደ።

ንጉሥ፡ዳዊትም፡ከኦርዮ፡ሚስት፡ሰሎሞንን፡ወለደ፤ ፯ ሰሎሞንም፡ሮብዓምን፡ወለደ፤ ሮብዓምም፡አቢያን፡ወለደ፤ አቢያም፡አሣፍን፡ወለደ፤ ፰ አሣፍም፡ኢዮሣፍጥን፡ወለደ፤ ኢዮሣፍጥም፡ኢዮራምን፡ወለደ፤ ኢዮራምም፡ዖዝያንን፡ወለደ፤ ፱ ዖዝያንም፡ኢዮአታምን፡ወለደ፤ ኢዮአታምም፡አካዝን፡ወለደ፤ ፲ አካዝም፡ሕዝቅያስን፡ወለደ፤ ሕዝቅያስም፡ምናሴን፡ወለደ፤ ምናሴም፡አሞፅን፡ወለደ፤ ፲፩ አሞፅም፡ኢዮስያስን፡ወለደ፤ ኢዮስያስም፡በባቢሎን፡ምርኮ፡ጊዜ፡ኢኮንያንንና፡ወንድሞቹን፡ወለደ።

፲፪ ከባቢሎንም፡ምርኮ፡በኋላ፡ኢኮንያን፡ሰላትያልን፡ወለደ፤ ሰላትያልም፡ዘሩባቤልን፡ወለደ፤ ፲፫ ዘሩባቤልም፡አብዩድን፡ወለደ፤ አብዩድም፡ኤልያቄምን፡ወለደ፤ ኤልያቄምም፡አዛርን፡ወለደ፤ ፲፬ አዛርም፡ሳዶቅን፡ወለደ፤ ሳዶቅም፡አኪምን፡ወለደ፤ አኪምም፡ኤልዩድን፡ወለደ፤ ፲፭ ኤልዩድም፡አልዓዛርን፡ወለደ፤ አልዓዛርም፡ማታንን፡ወለደ፤ ማታንም፡ያዕቆብን፡ወለደ፤ ፲፮ ያዕቆብም፡ክርስቶስ፡የተባለውን፡ኢየሱስን፡የወለደች፡የማርያምን፡እጮኛ፡ዮሴፍን፡ወለደ።

፲፯ እንግዲህ፡ትውልድ፡ሁሉ፡ከአብርሃም፡እስከ፡ዳዊት፡አሥራ፡አራት፡ትውልድ፥ ከዳዊትም፡እስከ፡ባቢሎን፡ምርኮ፡አሥራ፡አራት፡ትውልድ፥ ከባቢሎንም፡ምርኮ፡እስከ፡ክርስቶስ፡አሥራ፡አራት፡ትውልድ፡ነው።

፲፰ የኢየሱስ፡ክርስቶስም፡ልደት፡እንዲህ፡ነበረ። እናቱ፡ማርያም፡ለዮሴፍ፡በታጨች፡ጊዜ፡ሳይገናኙ፡ከመንፈስ፡ቅዱስ፡ፀንሳ፡ተገኘች። ፲፱ እጮኛዋ፡ዮሴፍም፡ጻድቅ፡ሆኖ፡ሊገልጣት፡ስላልወደደ፡በስውር፡ሊተዋት፡አሰበ። ፳ እርሱ፡ግን፡ይህን፡ሲያስብ፥ እነሆ፡የጌታ፡መልአክ፡በሕልም፡ታየው፥ እንዲህም፡አለ፦ የዳዊት፡ልጅ፡ዮሴፍ፡ሆይ፥ ከእርስዋ፡የተፀነሰው፡ከመንፈስ፡ቅዱስ፡ነውና፡እጮኛህን፡ማርያምን፡ለመውሰድ፡አትፍራ። ፳፩ ልጅም፡ትወልዳለች፤ እርሱ፡ሕዝቡን፡ከኃጢአታቸው፡ያድናቸዋልና፡ስሙን፡ኢየሱስ፡ትለዋለህ። ፳፪ በነቢይ፡ከጌታ፡ዘንድ፦

፳፫ እነሆ፥ ድንግል፡ትፀንሳለች፡ልጅም፡ትወልዳለች፥ ስሙንም፡አማኑኤል፡ይሉታል፡

የተባለው፡ይፈጸም፡ዘንድ፡ይህ፡ሁሉ፡ሆኖአል፥ ትርጓሜውም፦ እግዚአብሔር፡ከእኛ፡ጋር፡የሚል፡ነው። ፳፬ ዮሴፍም፡ከእንቅልፉ፡ነቅቶ፡የጌታ፡መልአክ፡እንዳዘዘው፡አደረገ፤ ፳፭ እጮኛውንም፡ወሰደ፤ የበኵር፡ልጅዋንም፡እስክትወልድ፡ድረስ፡አላወቃትም፤ ስሙንም፡ኢየሱስ፡አለው።

## ምዕራፍ፡፪።

፩ ኢየሱስም፡በይሁዳ፡ቤተ፡ልሔም፡በንጉሡ፡በሄሮድስ፡ዘመን፡በተወለደ፡ጊዜ፥ እነሆ፥ ሰብአ፡ሰገል፦ ፪ የተወለደው፡የአይሁድ፡ንጉሥ፡ወዴት፡ነው? ኮከቡን፡በምሥራቅ፡አይተን፡ልንሰግድለት፡መጥተናልና፡እያሉ፡ከምሥራቅ፡ወደ፡ኢየሩሳሌም፡መጡ። ፫ ንጉሡ፡ሄሮድስም፡ሰምቶ፡ደነገጠ፥ ኢየሩሳሌምም፡ሁሉ፡ከእርሱ፡ጋር፤ ፬ የካህናትንም፡አለቆች፡የሕዝቡንም፡ጻፎች፡ሁሉ፡ሰብስቦ፡ክርስቶስ፡ወዴት፡እንዲወለድ፡ጠየቃቸው። ፭ ፮ እነርሱም፦

እንቺ፡ቤተ፡ልሔም፥ የይሁዳ፡ምድር፥
ከይሁዳ፡ገዢዎች፡ከቶ፡አታንሺም፤ ሕዝቤን፡እስራኤልን፡የሚጠብቅ፡መስፍን፡
ከአንቺ፡ይወጣልና፡

ተብሎ፡በነቢይ፡እንዲህ፡ተጽፎአልና፡በይሁዳ፡ቤተ፡ልሔም፡ነው፡አሉት።

፯ ከዚህ፡በኋላ፡ሄሮድስ፡ሰብአ፡ሰገልን፡በስ

፩። ፩—፲፯፤ ሉቃ. ፫፥፳፫—፴፰። ፪፤ ዘፍጥ. ፳፩፥፫፤ ፳፭፥፳፮፤ ፳፱፥፴፭። ፫—፮፤ [illegible] ፲፮፥ [illegible] ። ፲፰፤ ሉቃ. ፩፥፳፯። [illegible] ሉቃ. ፪፥፳፩። [illegible] ። [illegible] ሉቃ. ፪፥፯። 
፪። ፩፤ ሉቃ. ፪፥፬—፯። ፪፤ [illegible] ። ፮፤ ሚክ. ፭፥፪።

ውር ፡ ጠርቶ ፡ ኮከቡ ፡ የታየበትን ፡ ዘመን ፡
፰ ከእነርሱ ፡ በጥንቃቄ ፡ ተረዳ ፤ ወደ ፡ ቤተ ፡
ልሔምም ፡ እነርሱን ፡ ሰድዶ ፡— ሂዱ ፤ ስለ ፡
ሕፃኑ ፡ በጥንቃቄ ፡ መርምሩ ፤ ባገኛችሁትም ፡
ጊዜ ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ መጥቼ ፡ እንድሰግድለት ፡
፱ ንገሩኝ ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡ ንጉሡን ፡ ሰም
ተው ፡ ሄዱ ፤ እነሆም ፤ በምሥራቅ ፡ ያዩት ፡
ኮከብ ፡ ሕፃኑ ፡ ባለበት ፡ ላይ ፡ መጥቶ ፡ እስኪ
፲ ቆም ፡ ድረስ ፡ ይመራቸው ፡ ነበር ። ኮከቡንም ፡
በዩ ፡ ጊዜ ፡ በታላቅ ፡ ደስታ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አላ
፲፩ ቸው ። ወደ ፡ ቤትም ፡ ገብተው ፡ ሕፃኑን ፡ ከእ
ናቱ ፡ ከማርያም ፡ ጋር ፡ አዩት ፤ ወድቀውም ፡
ሰገዱለት ፤ ሣጥኖቻቸውንም ፡ ከፍተው ፡ እጅ ፡
መንሻ ፡ ወርቅና ፡ ዕጣን ፡ ከርቤም ፡ አቀረቡለት ።
፲፪ ወደ ፡ ሄሮድስም ፡ እንዳይመለሱ ፡ በሕልም ፡ ተረ
ድተው ፡ በሌላ ፡ መንገድ ፡ ወደ ፡ አገራቸው ፡ ሄዱ ።
፲፫ እነርሱም ፡ ከሄዱ ፡ በኋላ ፡ እነሆ ፤ የጌታ ፡ መል
አክ ፡ በሕልም ፡ ለዮሴፍ ፡ ታይቶ ፡— ሄሮድስ ፡ ሕፃ
ኑን ፡ ሊገድለው ፡ ይፈልገዋልና ፡ ተነሣ ፤ ሕፃኑ
ንና ፡ እናቱንም ፡ ይዘህ ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ሽሽ ፤
እስክነግርህም ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ ተቀመጥ ፡ አለው ።
፲፬፲፭ እርሱም ፡ ተነሥቶ ፡ ሕፃኑንና ፡ እናቱን ፡ በሌ
ሊት ፡ ያዘና ፡ ከጌታ ፡ ዘንድ ፡ በነቢይ ፡— ልጄን ፡
ከግብፅ ፡ ጠራሁት ፡ የተባለው ፡ እንዲፈጸም ፡
ወደ ፡ ግብፅ ፡ ሄደ ፤ ሄሮድስም ፡ እስኪሞት ፡
ድረስ ፡ በዚያ ፡ ኖረ ።
፲፮ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሄሮድስ ፡ ሰብአ ፡ ሰገል ፡ እንደ
ተሣለቁበት ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ተቈጣና ፡
ልኮ ፡ ከሰብአ ፡ ሰገል ፡ እንደ ፡ ተረዳው ፡ ዘመን ፡
በቤተ ፡ ልሔምና ፡ በአውራጃዋ ፡ የነበሩትን ፤
ሁለት ፡ ዓመት ፡ የሆናቸውን ፡ ከዚያም ፡ የሚያ
፲፯፲፰ ንሱትን ፡ ሕፃናትን ፡ ሁሉ ፡ አስገደለ ። ያን ፡ ጊዜ ፡
በነቢዩ ፡ በኤርምያስ ፡—

> ድምፅ ፡ በራማ ፡ ተሰማ ፤ ልቅሶና ፡ ብዙ ፡
> ዋይታ ፤ ራሔል ፡ ስለ ፡ ልጆችዋ ፡ አለቀሰች ፤
> መጽናናትም ፡ አልወደደችም ፤ የሉምና ፡

የተባለው ፡ ተፈጸመ ።
፲፱ ሄሮድስም ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፤ እነሆ ፤ የጌታ ፡ መል
አክ ፡ በግብፅ ፡ ለዮሴፍ ፡ በሕልም ፡ ታይቶ ፡—
፳ የሕፃኑን ፡ ነፍስ ፡ የፈለጉት ፡ ሞተዋልና ፡ ተነሣ ፤
ሕፃኑን ፡ እናቱንም ፡ ይዘህ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡
፳፩ አገር ፡ ሂድ ፡ አለ ። እርሱም ፡ ተነሥቶ ፡ ሕፃኑ
ንና ፡ እናቱን ፡ ያዘና ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ አገር ፡
፳፪ ገባ ። በአባቱም ፡ በሄሮድስ ፡ ፈንታ ፡ አርኬላ
ዎስ ፡ በይሁዳ ፡ እንደ ፡ ነገሠ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፤ ወደ
ዚያ ፡ መሄድን ፡ ፈራ ፤ በሕልምም ፡ ተረድቶ ፡
፳፫ ወደ ፡ ገሊላ ፡ አገር ፡ ሄደ ፤ በነቢያት ፡— ናዝራዊ ፡
ይባላል ፡ የተባለው ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፤ ናዝ
ሬት ፡ ወደምትባል ፡ ከተማ ፡ መጥቶ ፡ ኖረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፪ በዚያም ፡ ወራት ፡ መጥምቁ ፡ ዮሐንስ ፡—
መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ቀርባለችና ፡ ንስሐ ፡ ግቡ ፡
ብሎ ፡ በይሁዳ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ እየሰበከ ፡ መጣ ።
፫ በነቢዩ ፡ በኢሳይያስ ፡—

> የጌታን ፡ መንገድ ፡ አዘጋጁ ፡ ጥርጊያው
> ንም ፡ አቅኑ ፡ እያለ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የሚ
> ጮህ ፡ ሰው ፡ ድምፅ ፡

፬ የተባለለት ፡ ይህ ፡ ነውና ። ራሱም ፡ ዮሐንስ ፡
የግመል ፡ ጠጕር ፡ ልብስ ፡ ነበረው ፡ በወገቡም ፡
ጠፍር ፡ ይታጠቅ ፡ ነበር ፤ ምግቡም ፡ አንበጣና ፡
፭ የበረሀ ፡ ማር ፡ ነበረ ። ያን ፡ ጊዜ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
ይሁዳም ፡ ሁሉ ፡ በዮርዳኖስም ፡ ዙሪያ ፡ ያለ ፡
፮ አገር ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ይወጡ ፡ ነበር ፤ ኃጢ
አታቸውንም ፡ እየተናዘዙ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ወንዝ ፡
ከእርሱ ፡ ይጠመቁ ፡ ነበር ።
፯ ዳሩ ፡ ግን ፡ ከፈሪሳውያንና ፡ ከሰዱቃውያን ፡
ብዙዎች ፡ ወደ ፡ ጥምቀቱ ፡ ሲመጡ ፡ በዩ ፡
ጊዜ ፤ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— እናንተ ፡ የእፉኝት ፡
ልጆች ፤ ከሚመጣው ፡ ቍጣ ፡ እንድትሸሹ ፡
፰ ማን ፡ አመለከታችሁ ? እንግዲህ ፡ ለንስሐ ፡ የሚ
፱ ገባ ፡ ፍሬ ፡ አድርጉ ፤ በልባችሁም ፡— አብርሃም ፡
አባት ፡ አለን ፡ እንደምትሉ ፡ አይምሰላችሁ ፤
እላችኋለሁና— ከነዚህ ፡ ድንጋዮች ፡ ለአብርሃም ፡
ልጆች ፡ ሊያስነሣለት ፡ እግዚአብሔር ፡ ይች
፲ ላል ። አሁንስ ፡ ምሳር ፡ በዛፎች ፡ ሥር ፡ ተቀም
ጦአል ፤ እንግዲህ ፡ መልካም ፡ ፍሬ ፡ የማያደርግ ፡
ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ይቈረጣል ፡ ወደ ፡ እሳትም ፡ ይጣላል ።
፲፩ እኔስ ፡ ለንስሐ ፡ በውኃ ፡ አጠምቃችኋለሁ ፤
ጫማውን ፡ እሸከም ፡ ዘንድ ፡ የማይገባኝ ፡
ከእኔ ፡ በኋላ ፡ የሚመጣው ፡ ግን ፡ ከእኔ ፡ ይልቅ ፡
ይበረታል ፤ እርሱ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በእሳ
፲፪ ትም ፡ ያጠምቃችኋል ፤ መንሹም ፡ በእጁ ፡ ነው ፤
አውድማውንም ፡ ፈጽሞ ፡ ያጠራል ፤ ስንዴው
ንም ፡ በጎተራው ፡ ይከታል ፤ ገለባውን ፡ ግን ፡
በማይጠፋ ፡ እሳት ፡ ያቃጥለዋል ።
፲፫ ያን ፡ ጊዜ ፡ ኢየሱስ ፡ በዮሐንስ ፡ ሊጠመቅ ፡ ከገ
፲፬ ሊላ ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡ መጣ ። ዮሐንስ ፡ ግን ፡—
እኔ ፡ በአንተ ፡ ልጠመቅ ፡ ያስፈልገኛል ፡ አንተም ፡
ወደ ፡ እኔ ፡ ትመጣለህን ? ብሎ ፡ ይከለክለው ፡
፲፭ ነበር ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡— አሁንስ ፡ ፍቀድ
ልኝ ፤ እንዲህ ፡ ጽድቅን ፡ ሁሉ ፡ መፈጸም ፡ ይገ
ባናልና ፡ አለው ። ያን ፡ ጊዜ ፡ ፈቀደለት ።
፲፮ ኢየሱስም ፡ ከተጠመቀ ፡ በኋላ ፡ ወዲያው ፡
ከውኃ ፡ ወጣ ፤ እነሆም ፤ ሰማያት ፡ ተከፈቱ ፡ የእ
ግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ እንደ ፡ ርግብ ፡ ሲወ
፲፯ ርድ ፡ በእርሱ ፡ ላይም ፡ ሲመጣ ፡ አየ ፤ እነሆም ፤
ድምፅ ፡ ከሰማያት ፡ መጥቶ ፡— በእርሱ ፡ ደስ ፡
የሚለኝ ፡ የምወደው ፡ ልጄ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አለ ።

፪ ። ፲፩ ፡ መዝ. ፸፪ ፡ ፲ ። ፲፭ ፡ ሆሴ. ፲፩ ፡ ፩ ። ፲፰ ፡ ኤር. ፴፩ ፡ ፲፭ ። ፳፫ ፡ ኢሳ. ፲፩ ፡ ፩ ።

፫ ። ፩—፲፪ ፡ ማር. ፩ ፡ ፩—፰ ፤ ሉቃ. ፫ ፡ ፩—፲፯ ። ፪ ፡ ም. ፬ ፡ ፲፯ ፤ ሉቃ. ፲ ፡ ፱ ። ፫ ፡ ኢሳ. ፵ ፡ ፫ ፤ ማር. ፲ ፡ ፫ ፤ ሉቃ. ፫ ፡ ፬ ፤ ዮሐ. ፩ ፡ ፳፫ ። ፬ ፡ ፪ ነገሥ. ፩ ፡ ፰ ። ፯ ፡ የሐዋ. ፲፫ ፡ ፳፬ ። ፱ ፡ ዮሐ. ፰ ፡ ፴፱ ። ፲ ፡ ም. ፯ ፡ ፲፱ ። ፲፩ ፡ ዮሐ. ፩ ፡ ፳፮ ፡ ፴፫ ፡ ፴፬ ። ፲፫—፲፯ ፤ ማር. ፩ ፡ ፱—፲፩ ፤ ሉቃ. ፫ ፡ ፳፩ ፡ ፳፪ ፤ ዮሐ. ፩ ፡ ፴፪—፴፬ ። ፲፯ ፡ ም. ፲፯ ፡ ፭ ፤ ዮሐ. ፲፪ ፡ ፳፰ ፤ መዝ. ፪ ፡ ፯ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ኢየሱስ ፡ ከዲያብሎስ ፡ ይፈተን ፡ ዘንድ ፡ መንፈስ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወሰደው ። ፪ አርባ ፡ ቀንና ፡ አርባ ፡ ሌሊትም ፡ ከጦመ ፡ በኋላ ፡ ተራበ ። ፫ ፈታኝም ፡ ቀርቦ ፡— የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ከሆንህ ፥ እነዚህ ፡ ድንጋዮች ፡ እንጀራ ፡ እንዲሆኑ ፡ በል ፡ አለው ። ፬ እርሱም ፡ መልሶ ፡— ሰው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ አፍ ፡ በሚወጣ ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ እንጂ ፡ በእንጀራ ፡ ብቻ ፡ አይኖርም ፡ ተብሎ ፡ ተጽፎአል ፡ አለው ። ፭ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ዲያብሎስ ፡ ወደ ፡ ቅድስት ፡ ከተማ ፡ ወሰደውና ፡ እርሱን ፡ በመቅደስ ፡ ጫፍ ፡ ላይ ፡ አቁሞ ፡—

፮ መላእክቱን ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ ያዝልሃል ፡ እግርህንም ፡ በድንጋይ ፡ ከቶ ፡ እንዳትሰናከል ፡
በእጃቸው ፡ ያነሡሃል ፡

ተብሎ ፡ ተጽፎአልና ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅስ ፡ ከሆንህ ፥ ወደ ፡ ታች ፡ ራስህን ፡ ወርውር ፡ አለው ። ፯ ኢየሱስም ፡— ጌታን ፡ አምላክህን ፡ አትፈታተነው ፡ ተብሎ ፡ ደግሞ ፡ ተጽፎአል ፡ አለው ። ፰ ደግሞ ፡ ዲያብሎስ ፡ እጅግ ፡ ረጅም ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ተራራ ፡ ወሰደው ፥ የዓለምንም ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ ክብራቸውንም ፡ አሳይቶ ፡— ፱ ወድቀህ ፡ ብትሰግድልኝ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ እሰጥሃለሁ ፡ አለው ። ፲ ያን ፡ ጊዜ ፡ ኢየሱስ ፡— ሂድ ፥ አንተ ፡ ሰይጣን ፤ ለጌታህ ፡ ለአምላክህ ፡ ስገድ ፡ እርሱንም ፡ ብቻ ፡ አምልክ ፡ ተብሎ ፡ ተጽፎአልና ፡ አለው ። ፲፩ ያን ፡ ጊዜ ፡ ዲያብሎስ ፡ ተወው ፥ እነሆም ፥ መላእክት ፡ ቀርበው ፡ ያገለግሉት ፡ ነበር ።

፲፪ ኢየሱስም ፡ ዮሐንስ ፡ አልፎ ፡ እንደ ፡ ተሰጠ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ ፈቀቅ ፡ ብሎ ፡ ሄደ ። ፲፫ ናዝሬትንም ፡ ትቶ ፡ በዛብሎንና ፡ በንፍታሌም ፡ አገር ፡ በባሕር ፡ አጠገብ ፡ ወደ ፡ አለችው ፡ ወደ ፡ ፲፬፡፲፭፡፲፮ ቅፍርናሆም ፡ መጥቶ ፡ኖረ ። በነቢዩም ፡ በኢሳይያስ ፡—

የዛብሎን ፡ ምድርና ፡ የንፍታሌም ፡ ምድር ፥ የባሕር ፡ መንገድ ፥ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፥ የአሕዛብ ፡ ገሊላ ፤ በጨለማ ፡ የተቀመጠው ፡ ሕዝብ ፡ታላቅ ፡ ብርሃን ፡ አየ ፥ በሞት ፡ አገርና ፡ ጥላ ፡ ለተቀመጡትም ፡ ብርሃን ፡ ወጣላቸው ፡

የተባለው ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ሆነ ። ፲፯ ከዚያ ፡ ዘመን ፡ጀምሮ ፡ ኢየሱስ ፡— መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ቀርባለችና ፡ ንስሐ ፡ ግቡ ፡ እያለ ፡ ይሰብክ ፡ ጀመር ።

፲፰ በገሊላ ፡ባሕር ፡ አጠገብ ፡ ሲመላለስም ፡ ሁለት ፡ ወንድማማች ፡ ጴጥሮስ ፡ የሚሉትን ፡ ስምዖንን ፡ ወንድሙንም ፡ እንድርያስን ፡ መረባቸውን ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ሲጥሉ ፡ አየ ፥ ዓሣ ፡ አጥማጆች ፡ ነበሩና ። ፲፱ እርሱም ፡— በኋላዬ ፡ ኑና ፡ ሰዎችን ፡ አጥማጆች ፡ እንድትሆኑ ፡ አደርጋችኋለሁ ፡ አላቸው ። ፳ ወዲያውም ፡ መረባቸውን ፡ትተው ፡ ተከተሉት ። ፳፩ ከዚያም ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ሌሎችን ፡ ሁለት ፡ ወንድማማች ፡ የዘብዴዎስን ፡ ልጅ ፡ ያዕቆብን ፡ ወንድሙንም ፡ ዮሐንስን ፡ ከአባታቸው ፡ ከዘብዴዎስ ፡ ጋር ፡ በታንኳ ፡ መረባቸውን ፡ ሲያበጁ ፡ አየ ፤ ጠራቸውም ። ፳፪ እነርሱም ፡ ወዲያው ፡ ታንኳይቱንና ፡ አባታቸውን ፡ ትተው ፡ ተከተሉት ።

፳፫ ኢየሱስም ፡ በምኵራቦቻቸው ፡ እያስተማረ ፡ የመንግሥትንም ፡ ወንጌል ፡ እየሰበከ ፡ በሕዝብም ፡ ያለውን ፡ደዌና ፡ ሕማም ፡ ሁሉ ፡ እየፈወሰ ፡ በገሊላ ፡ ሁሉ ፡ ይዞር ፡ ነበር ። ፳፬ ዝናውም ፡ ወደ ፡ ሶርያ ፡ ሁሉ ፡ ወጣ ፤ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ደዌና ፡ ሥቃይም ፡ ተይዘው ፡ የታመሙትን ፡ ሁሉ ፡ አጋንንትም ፡ ያደሩባቸውን ፡ በጨረቃም ፡ የሚነሣባቸውን ፡ሽባዎችንም ፡ወደ ፡ እርሱ ፡ አመጡ ፥ ፈወሳቸውም ። ፳፭ ከገሊላም ፡ ከአሥሩ ፡ ከተማም ፡ ከኢየሩሳሌምም ፡ ከይሁዳም ፡ ከዮርዳኖስም ፡ ማዶ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ተከተሉት ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ሕዝቡንም ፡ አይቶ ፡ ወደ ፡ ተራራ ፡ ወጣ ፤ በተቀመጠም ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀረቡ ፤ ፪ አፉንም ፡ ከፍቶ ፡ አስተማራቸው ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—

፫ በመንፈስ ፡ ድሆች ፡ የሆኑ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፥ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ የእነርሱ ፡ ናትና ።

፬ የሚያዝኑ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፥ መጽናናትን ፡ ያገኛሉና ።

፭ የዋሆች ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፥ ምድርን ፡ ይወርሳሉና ።

፮ ጽድቅን ፡ የሚራቡና ፡ የሚጠሙ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፥ ይጠግባሉና ።

፯ የሚምሩ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፥ ይማራሉና ።

፰ ልበ ፡ ንጹሖች ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፥ እግዚአብሔርን ፡ ያዩታልና ።

፱ የሚያስተራርቁ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፥ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ይባላሉና ።

፲ ስለ ፡ ጽድቅ ፡ የሚሰደዱ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፥ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ የእነርሱ ፡ ናትና ።

፲፩ ሲነቅፉአችሁና ፡ ሲያሳድዱአችሁ ፡ በእኔም ፡ ምክንያት ፡ ክፉውን ፡ ሁሉ ፡ በውሸት ፡ ሲናገሩባችሁ ፡ ብፁዓን ፡ ናችሁ ። ፲፪ ዋጋችሁ ፡ በሰማያት ፡ ታላቅ ፡ ነውና ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፥ ሐሤትም ፡ አድርጉ ፤ ከእናንተ ፡ በፊት ፡ የነበሩትን ፡ ነቢያትን ፡ እንዲሁ ፡ አሳድደዋቸዋልና ።

፬። ፩—፲፩ ፤ ማር. ፩፥፲፪ ፣ ፲፫ ፤ ሉቃ. ፬፥፩—፲፫ ። [illegible]

፭። [illegible]

፲፫ እናንተ ፡ የምድር ፡ ጨው ፡ ናችሁ ፤ ጨው ፡ አልጫ ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ በምን ፡ ይጣፍጣል ? ወደ ፡ ውጭ ፡ ተጥሎ ፡ በሰው ፡ ከመረገጥ ፡ በቀር ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ለምንም ፡ አይጠቅምም ።

፲፬ እናንተ ፡ የዓለም ፡ብርሃን ፡ ናችሁ ። በተራራ ፡ ላይ ፡ ያለች ፡ ከተማ ፡ ልትሰወር ፡ አይቻላትም ።
፲፭ መብራትንም ፡ አብርተው ፡ ከዕንቅብ ፡ በታች ፡ አይደለም ፡ እንጂ ፡ በመቅረዝ ፡ ላይ ፡ ያኖሩታል ፡
፲፮ በቤት ፡ ላሉት ፡ ሁሉም ፡ ያበራል ። መልካሙን ፡ ሥራችሁን ፡ አይተው ፡ በሰማያት ፡ ያለውን ፡ አባታችሁን ፡ እንዲያከብሩ ፡ ብርሃናችሁ ፡ እንዲሁ ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ ይብራ ።

፲፯ እኔ ፡ ሕግንና ፡ ነቢያትን ፡ ለመሻር ፡ የመጣሁ ፡ አይምሰላችሁ ፤ ልፈጽም ፡ እንጂ ፡ ለመሻር ፡ አል
፲፰ መጣሁም ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ፤ ሰማይና ፡ ምድር ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፤ ከሕግ ፡ አንዲት ፡ የውጣ ፡ ወይም ፡ አንዲት ፡ ነጥብ ፡ ከቶ ፡ አታል
፲፱ ፍም ፤ ሁሉ ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ። እንግዲህ ፡ ከነዚህ ፡ ከሁሉ ፡ ካነሉት ፡ ትእዛዛት ፡ አንዲቱን ፡ የሚሽር ፡ ለሰውም ፡ እንዲሁ ፡ የሚያስተምር ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ከሁሉ ፡ ታናሽ ፡ ይባላል ፤ የሚያደርግ ፡ ግን ፡ የሚያስተምርም ፡ ማንም ፡ ቢሆን ፡ እርሱ ፡ በመንግሥተ ፡
፳ ሰማያት ፡ ታላቅ ፡ ይባላል ። እላችኋለሁና ፤— ጽድቃችሁ ፡ ከጻፎችና ፡ ከፈሪሳውያን ፡ ጽድቅ ፡ ካልበለጠ ፤ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ከቶ ፡ አትገቡም ።

፳፩ ለቀደሙት ፡ –አትግደል ፡ እንደ ፡ ተባለ ፡ ሰምታችኋል ፤ የገደለም ፡ ሁሉ ፡ ፍርድ ፡ ይገባዋል ።
፳፪ እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፤ በወንድሙ ፡ ላይ ፡ የሚቈጣ ፡ ሁሉ ፡ ፍርድ ፡ ይገባዋል ፤ ወንድሙንም ፡ ጨርቃም ፡ የሚለው ፡ ሁሉ ፡ የሸንጎ ፡ ፍርድ ፡ ይገባዋል ፤ ደንቆሮ ፡ የሚለውም ፡ ሁሉ ፡ የገሃነመ ፡
፳፫ እሳት ፡ ፍርድ ፡ ይገባዋል ። እንግዲህ ፡ መባህን ፡ በመሠዊያው ፡ ላይ ፡ ብታቀርብ ፤ በዚያም ፡ ወንድምህ ፡ አንዳች ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ እንዳለው ፡
፳፬ ብታስብ ፤ በዚያ ፡ በመሠዊያው ፡ ፊት ፡ መባህን ፡ ትተህ ፡ ሂድ ፤ አስቀድመህም ፡ ከወንድምህ ፡ ጋር ፡ ታረቅ ፤ በኋላም ፡ መጥተህ ፡ መባህን ፡
፳፭ አቅርብ ። አብረኸው ፡ በመንገድ ፡ሳለህ ፡ ከባላጋራህ ፡ ጋር ፡ ፈጥነህ ፡ ተስማማ ፤ ባለጋራ ፡ ለዳኛ ፡ እንዳይሰጥህ ፡ ዳኛም ፡ ለሎሌው ፤ ወደ ፡ ወህ
፳፮ ኒም ፡ ትጣልለህ ፤ እውነት ፡ እልሃለሁ ፤ የመጨረሻዋን ፡ ሳንቲም ፡ እስክትከፍል ፡ ድረስ ፡ ከቶ ፡ ከዚያ ፡ አትወጣም ።

፳፯ አታመንዝር ፡ እንደ ፡ ተባለ ፡ ሰምታችኋል ።
፳፰ እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፤ ወደ ፡ ሴት ፡ ያየ ፡ ሁሉ ፡ የተመኛትም ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ በልቡ ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ አመንዝሮአል ።
፳፱ ቀኝ ፡ ዓይንህም ፡ ብታሰናክልህ ፡ አውጥተህ ፡ ከአንተ ፡ ጣላት ፤ሙሉ ፡ ሰውነትህ ፡ በገሃነም ፡ ከሚጣል ፡ ይልቅ ፡ ከአካላትህ ፡ አንድ ፡ ቢጠፋ ፡ ይሻልሃልና ።
፴ ቀኝ ፡ እጅህም ፡ ብታሰናክልህ ፡ ቈርጠህ ፡ ከአንተ ፡ ጣላት ፤ ሙሉ ፡ ሰውነትህ ፡ በገሃነም ፡ ከሚጣል ፡ ይልቅ ፡ ከአካላትህ ፡ አንድ ፡ ቢጠፋ ፡ ይሻላልና ።

፴፩ ሚስቱን ፡ የሚፈታት ፡ ሁሉ ፡ የፍችዋን ፡ጽሕፈት ፡ ይስጣት ፡ ተባለ ።
፴፪ እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፤ ያለ ፡ ዝሙት ፡ ምክንያት ፡ ሚስቱን ፡ የሚፈታ ፡ ሁሉ ፡ አመንዝራ ፡ ያደርጋታል ፤ የተፈታችውንም ፡ የሚያገባ ፡ ሁሉ ፡ ያመነዝራል ።

፴፫ ደግሞ ፡ ለቀደሙት ፡— በውሸት ፡ አትማል ፡ ነገር ፡ ግን ፡ መሐላዎችህን ፡ ለጌታ ፡ ስጥ ፡ እንደ ፡
፴፬ ተባለ ፡ ሰምታችኋል ። እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፡— ከቶ ፡ አትማሉ ፤ በሰማይ ፡ አይሆንም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ዙፋን ፡ ነውና ፤
፴፭ በምድርም ፡ አይሆንም ፡ የእግሩ ፡ መረገጫ ፡ ናትና ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ አይሆንም ፡ የታላቁ ፡ ንጉሥ ፡ ከተማ ፡
፴፮ ናትና ፤ በራስህም ፡ አትማል ፤ አንዲቱን ፡ጠጉር ፡ ነጭ ፡ ወይም ፡ ጥቁር ፡ ልታደርግ ፡ አትችል
፴፯ ምና ። ነገር ፡ ግን ፡ ቃላችሁ ፡ አዎን ፡ አዎን ፡ ወይም ፡ አይደለም ፡ አይደለም ፡ ይሁን ፤ ከነዚህም ፡ የወጣ ፡ ከክፉው ፡ ነው ።

፴፰ ዓይን ፡ ስለ ፡ ዓይን ፡ ጥርስም ፡ ስለ ፡ ጥርስ ፡ እንደ ፡ ተባለ ፡ ሰምታችኋል ።
፴፱ እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፤ ክፉውን ፡ አትቃወሙ ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ ቀኝ ፡ ጕንጭህን ፡ በጥፊ ፡ ለሚመታህ ፡ ሁሉ ፡ ሁለተኛውን ፡ ደግሞ ፡ አዙርለት ፤
፵ እንዲከስህም ፡ እጀ ፡ ጠባብህንም ፡ እንዲወስድ ፡ ለሚወድ ፡ መጐናጸፊያህን ፡ ደግሞ ፡ ተውለት ፤
፵፩ ማንም ፡ ሰው ፡ አንድ ፡ ምዕራፍ ፡ ትሄድ ፡ ዘንድ ፡ ቢያስገድድህ ፡ ሁለተኛውን ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሂድ ።
፵፪ ለሚለምንህ ፡ ስጥ ፤ ከአንተም ፡ ይበደር ፡ ዘንድ ፡ ከሚወደው ፡ ፊቱን ፡ አትመልስ ።

፵፫ ባልንጀራህን ፡ ውደድ ፡ ጠላትህንም ፡ ጥላ ፡ እንደ ፡ ተባለ ፡ ሰምታችኋል ።
፵፬ እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፤ በሰማያት ፡ ላለ ፡ አባታችሁ ፡ ልጆች ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ጠላቶቻችሁን ፡ ውደዱ ፤ የሚረግሙአችሁንም ፡ መርቁ ፤ ለሚጠሉአችሁም ፡ መልካም ፡ አድርጉ ፤ ስለሚያሳድዱአችሁም ፡
፵፭ ጸልዩ ፤ እርሱ ፡ በክፉዎችና ፡ በበጎዎች ፡ ላይ ፡ ፀሐዩን ፡ ያወጣልና ፤ በጻድቃንና ፡ በኃጢአተኞችም ፡ ላይ ፡ ዝናቡን ፡ ያዘንባልና ።
፵፮ የሚወዱ

፭ ። ፲፫ ፤ ማር. ፱ ፡ [illegible] ፤ ሉቃ. [illegible] ። ፲፬ ፤ ዮሐ. [illegible] ። ፲፭ ፤ ማር. [illegible] ፤ ሉቃ. [illegible] ። ፲፮ ፤ ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ዘፀአ. [illegible] ፤ ዘሌዋ. [illegible] ። [illegible] ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ዘፀአ. [illegible] ። [illegible] ኢዮብ [illegible] ። [illegible] ማር. [illegible] ፤ ሮሜ. [illegible] ። [illegible] ዘዳግ. [illegible] ፤ ማር. [illegible] ፤ ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ዘሌዋ. [illegible] ፤ ዘኍል. [illegible] ። [illegible] ኢሳ. [illegible] ። [illegible] መዝ. [illegible] ። [illegible] ዘፀአ. [illegible] ። [illegible] ሉቃ. [illegible] ፤ ሮሜ. [illegible] ። [illegible] ዘዳግ. [illegible] ፤ ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ዘሌዋ. [illegible] ። [illegible] ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ሉቃ. [illegible] ።

እችሁን ፡ ብትወዱ ፡ ምን ፡ ዋጋ ፡ አላችሁ ? ቀራጮችስ ፡ ያንኑ ፡ ያደርጉ ፡ የለምን ? **፵፯** ወንድሞቻችሁንም ፡ ብቻ ፡ እጅ ፡ ብትነሡ ፡ ምን ፡ ብልጫ ፡ ታደርጋላችሁ ? አሕዛብስ ፡ ያንኑ ፡ ያደርጉ ፡ የለምን ? **፵፰** እንግዲህ ፡ የሰማዩ ፡ አባታችሁ ፡ ፍጹም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እናንተ ፡ ፍጹማን ፡ ሁኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

**፩** ለሰዎች ፡ ትታዩ ፡ ዘንድ ፡ <u>ምጽዋታችሁን</u> ፡ በፊታቸው ፡ እንዳታደርጉ ፡ ተጠንቀቁ ፤ ያለዚያ ፡ በሰማያት ፡ ባለው ፡ አባታችሁ ፡ ዘንድ ፡ ዋጋ ፡ የላችሁም ።

**፪** እንግዲህ ፡ ምጽዋት ፡ ስታደርግ ፥ ግብዞች ፡ በሰው ፡ ዘንድ ፡ ሊከበሩ ፡ በምኵራብ ፡ በመንገድም ፡ እንደሚያደርጉ ፡ በፊትህ ፡ መለከት ፡ አታስነፋ ፤ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ዋጋቸውን ፡ ተቀ **፫፡፬** ብለዋል ። አንተ ፡ ግን ፡ ምጽዋት ፡ ስታደርግ ፡ ምጽዋትህ ፡ በስውር ፡ እንዲሆን ፡ ቀኝህ ፡ የምትሠራውን ፡ ግራህ ፡ አትወቅ ፤ በስውር ፡ የሚያይ ፡ አባትህም ፡ በግልጥ ፡ ይከፍልሃል ።

**፭** ስትጸልዩም ፡ እንደ ፡ ግብዞች ፡ አትሁኑ ፤ ለሰው ፡ ይታዩ ፡ ዘንድ ፡ በምኵራብና ፡ በመንገድ ፡ ማዕዘን ፡ ቆመው ፡ መጸለይን ፡ ይወዳሉና ፤ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ዋጋቸውን ፡ ተቀብለዋል ።
**፮** አንተ ፡ ግን ፡ ስትጸልይ ፥ ወደ ፡ እልፍኝህ ፡ ግባ ፡ መዝጊያህንም ፡ ዘግተህ ፡ በስውር ፡ ላለው ፡ አባትህ ፡ ጸልይ ፤ በስውር ፡ የሚያይ ፡ አባትህም ፡ በግልጥ ፡ ይከፍልሃል ።

**፯** አሕዛብም ፡ በመናገራቸው ፡ ብዛት ፡ እንዲሰሙ ፡ ይመስላቸዋልና ፡ ስትጸልዩ ፡ እንደ ፡ እነርሱ ፡ **፰** በከንቱ ፡ አትድገሙ ። ስለዚህ ፡ አትምሰሉአቸው ፤ ሳትለምኑት ፡ አባታችሁ ፡ የሚያስፈልጋ **፱** ችሁን ፡ ያውቃልና ። እንግዲህ ፡ እናንተስ ፡ እንዲህ ፡ ጸልዩ ፡— በሰማያት ፡ የምትኖር ፡ አባታ **፲** ችን ፡ ሆይ ፥ ስምህ ፡ ይቀደስ ፤ መንግሥትህ ፡ ትምጣ ፤ ፈቃድህ ፡ በሰማይ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ እንዲሁ ፡ **፲፩** በምድር ፡ ትሁን ፤ የዕለት ፡ እንጀራችንን ፡ ዛሬ ፡ **፲፪** ስጠን ፤ እኛም ፡ ደግሞ ፡ የበደሉንን ፡ ይቅር ፡ **፲፫** እንደምንል ፡ በደላችንን ፡ ይቅር ፡ በለን ፤ ከክፉም ፡ አድነን ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ፈተና ፡ አታግባን ፤ መንግሥት ፡ ያንተ ፡ ናትና ፡ ኃይልም ፡ ክብርም ፡ **፲፬** ለዘለዓለሙ ፤ አሜን ። ለሰዎች ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ይቅር ፡ ብትሉ ፥ የሰማዩ ፡ አባታችሁ ፡ እና **፲፭** ንተን ፡ ደግሞ ፡ ይቅር ፡ ይላችኋልና ፤ ለሰዎች ፡ ግን ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ይቅር ፡ ባትሉ ፥ አባታችሁም ፡ ኃጢአታችሁን ፡ ይቅር ፡ አይላችሁም ።

**፲፮** ስትጦሙም ፥ እንደ ፡ ግብዞች ፡ አትጠውልጉ ፤ ለሰዎች ፡ እንደ ፡ ጦመኛ ፡ ሊታዩ ፡ ፊታቸውን ፡ ያጠፋሉና ፤ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ዋጋቸውን ፡ **፲፯፡፲፰** ተቀብለዋል ። አንተ ፡ ግን ፡ ስትጦም ፥ በስውር ፡ ላለው ፡ አባትህ ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ ጦመኛ ፡ ለሰዎች ፡ እንዳትታይ ፡ ራስህን ፡ ቅባ ፡ ፊትህንም ፡ ታጠብ ፤ በስውር ፡ የሚያይ ፡ አባትህም ፡ በግልጥ ፡ ይከፍልሃል ።

**፲፱** ብልና ፡ ዝገት ፡ በሚያጠፉት ፡ ሌቦችም ፡ ቈፍረው ፡ በሚሰርቁት ፡ ዘንድ ፡ ለእናንተ ፡ በምድር ፡ **፳** ላይ ፡ መዝገብ ፡ አትሰብስቡ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ብልም ፡ ዝገትም ፡ በማያጠፉት ፡ ሌቦችም ፡ ቈፍረው ፡ በማይሰርቁት ፡ ዘንድ ፡ ለእናንተ ፡ በሰማይ ፡ መዝ **፳፩** ገብ ፡ ሰብስቡ ! መዝገብህ ፡ ባለበት ፡ ልብህ ፡ ደግሞ ፡ በዚያ ፡ ይሆናልና ።

**፳፪** የሰውነት ፡ መብራት ፡ ዓይን ፡ ናት ። ዓይንህ ፡ እንግዲህ ፡ ጤናማ ፡ ብትሆን ፥ ሰውነትህ ፡ ሁሉ ፡ **፳፫** ብሩህ ፡ ይሆናል ፤ ዓይንህ ፡ ግን ፡ ታማሚ ፡ ብትሆን ፥ ሰውነትህ ፡ ሁሉ ፡ የጨለመ ፡ ይሆናል ። እንግዲህ ፡ በአንተ ፡ ያለው ፡ ብርሃን ፡ ጨለማ ፡ ከሆነ ፥ ጨለማውስ ፡ እንዴት ፡ ይበረታ !

**፳፬** ለሁለት ፡ ጌቶች ፡ መገዛት ፡ የሚቻለው ፡ ማንም ፡ የለም ፤ ወይም ፡ አንዱን ፡ ይጠላል ፡ ሁለተኛውንም ፡ ይወዳል ፤ ወይም ፡ ወደ ፡ አንዱ ፡ ይጠጋል ፡ ሁለተኛውንም ፡ ይንቃል ፤ ለእግዚአብሔርና ፡ ለገንዘብ ፡ መገዛት ፡ አትችሉም ።

**፳፭** ስለዚህ ፡ እላችኋለሁ ፥ ስለ ፡ ነፍሳችሁ ፡ በምትበሉትና ፡ በምትጠጡት ፥ ወይም ፡ ስለ ፡ ሰውነታችሁ ፡ በምትለብሱት ፡ አትጨነቁ ፤ ነፍስ ፡ ከመብል ፡ ሰውነትም ፡ ከልብስ ፡ አይበልጥምን ? **፳፮** ወደ ፡ ሰማይ ፡ ወፎች ፡ ተመልከቱ ፤ አይዘሩም ፡ አያጭዱምም ፡ በጎተራም ፡ አይከቱም ፥ የሰማዩ ፡ አባታችሁም ፡ ይመግባቸዋል ፤ እናንተ ፡ ከእነ **፳፯** ርሱ ፡ እጅግ ፡ አትበልጡምን ? ከእናንተ ፡ ተጨንቆ ፡ በቁመቱ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ መጨመር ፡ **፳፰** የሚችል ፡ ማን ፡ ነው ? ስለ ፡ ልብስስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትጨነቃላችሁ ? የሜዳ ፡ አበቦች ፡ እንዴት ፡ እንዲያድጉ ፡ ልብ ፡ አድርጋችሁ ፡ ተመልከቱ ፤ **፳፱** አይደክሙም ፡ አይፈትሉምም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፥ ሰሎሞንስ ፡ እንኳ ፡ በክብሩ ፡ ሁሉ ፡ **፴** ከነዚህ ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ አልለበሰም ። እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ዛሬ ፡ ያለውን ፡ ነገም ፡ ወደ ፡ እቶን ፡ የሚጣለውን ፡ የሜዳን ፡ ሣር ፡ እንዲህ ፡ የሚያለብሰው ፡ ከሆነ ፥ እናንተ ፡ እምነት ፡ የጐደላችሁ ፥ **፴፩** እናንተንማ ፡ ይልቁን ፡ እንዴት ? እንግዲህ ፡— ምን ፡ እንበላለን ? ምንስ ፡ እንጠጣለን ? ምንስ ፡ **፴፪** እንለብሳለን ? ብላችሁ ፡ አትጨነቁ ፤ ይህንስ ፡ ሁሉ ፡ አሕዛብ ፡ ይፈልጋሉ ፤ ይህ ፡ ሁሉ ፡ እንዲያስፈልጋችሁ ፡ የሰማዩ ፡ አባታችሁ ፡ ያውቃ **፴፫** ልና ። ነገር ፡ ግን ፡ አስቀድማችሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ ጽድቁንም ፡ ፈልጉ ፤ ይህም ፡ ሁሉ ፡ ይጨመርላችኋል ።

**፴፬** ነገ ፡ ለራሱ ፡ ይጨነቃልና ፡ ለነገ ፡ አትጨነቁ ፤ ለቀኑ ፡ ክፋቱ ፡ ይበቃዋል ።

[illegible]

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩፤ እንዳይፈረድባችሁ ፡ አትፍረዱ ፤ ፪ በምትፈርዱበት ፡ ፍርድ ፡ ይፈረድባችኋልና ፥ በምትሰፍሩበትም ፡ መስፈሪያ ፡ ይሰፈርባችኋል ። ፫ በወንድምህም ፡ ዓይን ፡ ያለውን ፡ ጕድፍ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ታያለህ ፥ በዓይንህ ፡ ግን ፡ ያለውን ፡ ምሰሶ ፡ ፬ ስለ ፡ ምን ፡ አትመለከትም ? ወይም ፡ ወንድምህን ፦ ከዓይንህ ፡ ጕድፍ ፡ ላውጣ ፡ ፍቀድልኝ ፡ እንዴት ፡ ትለዋለህ ? እነሆም ፡ በዓይንህ ፡ ፭ ምሰሶ ፡ አለ ። እንተ ፡ ግብዝ ፥ አስቀድመህ ፡ ከዓይንህ ፡ ምሰሶውን ፡ አውጣ ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ከወንድምህ ፡ ዓይን ፡ ጕድፉን ፡ ታወጣ ፡ ዘንድ ፡ አጥርተህ ፡ ታያለህ ።

፮ በእግራቸው ፡ እንዳይረግጡት ፡ ተመልሰውም ፡ እንዳይነክሱአችሁ ፥ የተቀደሰውን ፡ ለውሾች ፡ አትስጡ ፥ ዕንቍቻችሁንም ፡ በእሪያዎች ፡ ፊት ፡ አትጣሉ ።

፯ ለምኑ ፥ ይሰጣችሁማል ፤ ፈልጉ ፥ ታገኙማላችሁ ፤ መዝጊያን ፡ እንኳኩ ፥ ይከፈትላችሁ ፰ ማል ። የሚለምነው ፡ ሁሉ ፡ ይቀበላልና ፥ የሚፈልገውም ፡ ያገኛል ፥ መዝጊያንም ፡ ለሚያ ፱ ንኳኳ ፡ ይከፈትለታል ። ወይስ ፡ ከእናንተ ፥ ልጁ ፡ እንጀራ ፡ ቢለምነው ፥ ድንጋይን ፡ የሚሰ ፲ ጠው ፡ ከእናንተ ፡ ማን ፡ ሰው ፡ ነው ? ዓሣስ ፡ ፲፩ ቢለምነው ፡ እባብን ፡ ይሰጠዋልን ? እንኪያስ ፡ እናንተ ፡ ክፉዎች ፡ ስትሆኑ ፡ ለልጆቻችሁ ፡ መልካም ፡ ስጦታ ፡ መስጠትን ፡ ካወቃችሁ ፥ በሰማያት ፡ ያለው ፡ አባታችሁ ፡ ለሚለምኑት ፡ እንዴት ፡ አብልጦ ፡ መልካም ፡ ነገርን ፡ ይሰ ፲፪ ጣቸው ? እንግዲህ ፡ ሰዎች ፡ ሊያደርጉላችሁ ፡ የምትወዱትን ፡ ሁሉ ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ እንዲሁ ፡ አድርጉላቸው ፤ ሕግም ፡ ነቢያትም ፡ ይህ ፡ ነውና ።

፲፫ በጠበበው ፡ ደጅ ፡ ግቡ ፤ ወደ ፡ ጥፋት ፡ የሚወስደው ፡ ደጅ ፡ ሰፊ ፥ መንገዱም ፡ ትልቅ ፡ ነውና ፥ ወደ ፡ እርሱም ፡ የሚገቡ ፡ ብዙዎች ፡ ናቸው ፤ ፲፬ ወደ ፡ ሕይወት ፡ የሚወስደው ፡ ደጅ ፡ የጠበበ ፥ መንገዱም ፡ የቀጠነ ፡ ነውና ፥ የሚያገኙትም ፡ ጥቂቶች ፡ ናቸው ።

፲፭ የበግ ፡ ለምድ ፡ ለብሰው ፡ ከሚመጡባችሁ ፡ በውስጣቸው ፡ ግን ፡ ነጣቂዎች ፡ ተኵላዎች ፡ ፲፮ ከሆኑ ፡ ከሐሰተኞች ፡ ነቢያት ፡ ተጠንቀቁ ። ከፍሬያቸው ፡ ታውቁአቸዋላችሁ ። ከእሾህ ፡ ወይን ፥ ፲፯ ከኵርንችትስ ፡ በለስ ፡ ይለቀማልን ? እንዲሁ ፡ መልካም ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ መልካም ፡ ፍሬ ፡ ያደርጋል ፥ ክፉም ፡ ዛፍ ፡ ክፉ ፡ ፍሬ ፡ ያደርጋል ። ፲፰ መልካም ፡ ዛፍ ፡ ክፉ ፡ ፍሬ ፡ ማፍራት ፥ ወይም ፡ ክፉ ፡ ዛፍ ፡ መልካም ፡ ፍሬ ፡ ማፍራት ፡ አይቻለውም ። ፲፱ መልካም ፡ ፍሬ ፡ የማያደርግ ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ይቈረጣል ፡ ወደ ፡ እሳትም ፡ ይጣላል ። ፳ ስለዚህም ፡ ከፍሬያቸው ፡ ታውቁአቸዋላችሁ ።

፳፩ በሰማያት ፡ ያለውን ፡ የአባቴን ፡ ፈቃድ ፡ የሚያደርግ ፡ እንጂ ፥ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ጌታ ፡ ሆይ ፥ የሚለኝ ፡ ሁሉ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ የሚገባ ፡ አይደለም ። ፳፪ በዚያ ፡ ቀን ፡ ብዙዎች ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ጌታ ፡ ሆይ ፥ በስምህ ፡ ትንቢት ፡ አልተናገርንምን ፥ በስምህስ ፡ አጋንንትን ፡ አላወጣንምን ፥ በስምህስ ፡ ብዙ ፡ ተአምራት ፡ አላደረግንምን ? ይሉኛል ። ፳፫ የዚያን ፡ ጊዜም ፦ ከቶ ፡ አላወቅኋችሁም ፤ እናንተ ፡ ዓመፀኞች ፥ ከእኔ ፡ ራቁ ፡ ብዬ ፡ አመሰክርባቸዋለሁ ።

፳፬ ስለዚህ ፡ ይህን ፡ ቃሌን ፡ ሰምቶ ፡ የሚያደርገው ፡ ሁሉ ፡ ቤቱን ፡ በዓለት ፡ ላይ ፡ የሠራ ፡ ልባም ፡ ሰውን ፡ ይመስላል ። ፳፭ ዝናብም ፡ ወረደ ፡ ጐርፍም ፡ መጣ ፡ ነፋስም ፡ ነፈሰ ፡ ያንም ፡ ቤት ፡ ገፋው ፥ በዓለት ፡ ላይም ፡ ስለ ፡ ተመሠረተ ፡ አልወደቀም ። ፳፮ ይህንም ፡ ቃሌን ፡ ሰምቶ ፡ የማያደርገው ፡ ሁሉ ፡ ቤቱን ፡ በአሸዋ ፡ ላይ ፡ የሠራ ፡ ሰነፍ ፡ ሰውን ፡ ይመስላል ። ፳፯ ዝናብም ፡ ወረደ ፡ ጐርፍም ፡ መጣ ፡ ነፋስም ፡ ነፈሰ ፡ ያንም ፡ ቤት ፡ መታው ፥ ወደቀም ፥ አወዳደቁም ፡ ታላቅ ፡ ሆነ ።

፳፰ ኢየሱስም ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ በጨረሰ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡ ፡ በትምህርቱ ፡ ተገረሙ ፤ እንደ ፡ ጻፎቻ ፳፱ ቸው ፡ ሳይሆን ፡ እንደ ፡ ባለ ፡ ሥልጣን ፡ ያስተምራቸው ፡ ነበርና ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ ከተራራም ፡ በወረደ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ተከተሉት ። ፪ እነሆም ፥ ለምጻም ፡ ቀርቦ ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ብትወድስ ፡ ልታነጻኝ ፡ ትችላለህ ፡ እያለ ፡ ሰገደለት ። ፫ እጁንም ፡ ዘርግቶ ፡ ዳሰሰውና ፦ እወዳለሁ ፥ ንጻ ፡ አለው ። ወዲያውም ፡ ለምጹ ፡ ነጻ ። ፬ ኢየሱስም ፦ ለማንም ፡ እንዳትናገር ፡ ተጠንቀቅ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ሄደህ ፡ ራስህን ፡ ለካህን ፡ አሳይ ፥ ለእነርሱም ፡ ምስክር ፡ እንዲሆን ፡ ሙሴ ፡ ያዘዘውን ፡ መባ ፡ አቅርብ ፡ አለው ።

፭ ወደ ፡ ቅፍርናሆምም ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ የመቶ ፡ አለቃ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀርቦ ፦ ፮ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ብላቴናዬ ፡ ሽባ ፡ ሆኖ ፡ እጅግ ፡ እየተሣቀየ ፡ በቤት ፡ ተኝቶአል ፡ ብሎ ፡ ለመነው ። ፯ ኢየሱስም ፦ እኔ ፡ መጥቼ ፡ እፈውሰዋለሁ ፡ አለው ። ፰ የመቶ ፡ አለቃውም ፡ መለሰ ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ በቤቴ ፡ ጣራ ፡ ከታች ፡ ልትገባ ፡ አይገባኝም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ቃል ፡

፯። ፩—፭፤ ሉቃ. ፮፥፴፯፡፴፰፡፵፩፡፵፪ ። ፪፤ ማር. ፬፥፳፬ ። ፯—፲፩፤ ሉቃ. ፲፩፥፱—፲፫፤ ማቴ. ፳፩፥፳፪፤ ማር. ፲፩፥፳፬፤ ዮሐ. ፲፬፥፲፫ ። ፲፪፤ ሉቃ. ፮፥፴፩ ። ፲፫፤ ሉቃ. ፲፫፥፳፬ ። ፲፭፤ ሮሜ. ፲፮፥፲፯ ። ፲፮፤ ሉቃ. ፮፥፵፬ ። ፲፮—፳፤ ማቴ. ፲፪፥፴፫ ። ፲፱፤ ሉቃ. ፫፥፱ ። ፳፩፤ ሮሜ. ፪፥፲፫ ። ፳፩፤ ሉቃ. ፮፥፵፮ ። ፳፪—፳፫፤ ሉቃ. ፲፫፥፳፮—፳፯ ። ፳፬—፳፯፤ ሉቃ. ፮፥፵፯—፵፱ ። ፳፰፡፳፱፤ ማቴ. ፲፫፥፶፬፤ ማር. ፩፥፳፪፤ ሉቃ. ፬፥፴፪፤ ዮሐ. ፯፥፵፮ ።

፰። ፩፤ ... ፪—፬፤ ማር. ፩፥፵—፵፬፤ ሉቃ. ፭፥፲፪—፲፬ ። ፬፤ ... ፲፬፥፲፭፤ ማር. ፩፥፵፬፤ ዘሌዋ. ፲፬ ፥ ፪—፴፪ ። ፭—፲፫፤ ሉቃ. ፯፥፩—፲ ።

፱ ብቻ ፡ ተናገር ፥ ብላቴናዬም ፡ ይፈወሳል ። እኔ ፡ ደግሞ ፡ ለሌሎች ፡ ተገዢ ፡ ነኝና ፥ ከእኔም ፡ በታች ፡ ጭፍራ ፡ አለኝ ፤ አንዱንም ፦ ሂድ ፡ ብለው ፡ ይሄዳል ፥ ሌላውንም ፦ ና ፡ ብለው ፡ ይመጣል ፥ ባሪያዬንም ፦ ይህን ፡ አድርግ ፡ ብለው ፡ ያደርጋል ፡ አለው ።
፲ ኢየሱስም ፡ ሰምቶ ፡ ተደነቀና ፡ ለተከተሉት ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ በእስራኤል ፡ እንኳ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ትልቅ ፡ እምነት ፡ አላገኘሁም ።
፲፩ እላችኋለሁም ፥ ብዙዎች ፡ ከምሥራቅና ፡ ከምዕራብ ፡ ይመጣሉ ፡ ከአብርሃምና ፡ ከይስሐቅ ፡ ከያዕቆብም ፡ ጋር ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ይቀመጣሉ ፤
፲፪ የመንግሥት ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ በውጭ ፡ ወደ ፡ አለው ፡ ጨለማ ፡ ይጣላሉ ፤ በዚያ ፡ ልቅሶና ፡ ጥርስ ፡ ማፏጨት ፡ ይሆናል ።
፲፫ ኢየሱስም ፡ ለመቶ ፡ አለቃ ፦ ሂድና ፡ እንዳመንህ ፡ ይሁንልህ ፡ አለው ። ብላቴናውም ፡ በዚያች ፡ ሰዓት ፡ ተፈወሰ ።
፲፬ ኢየሱስም ፡ ወደ ፡ ጴጥሮስ ፡ ቤት ፡ ገብቶ ፡ አማቱን ፡ በንዳድ ፡ ታማ ፡ ተኝታ ፡ አያት ፤
፲፭ እጅዋንም ፡ ዳሰሰ ፥ ንዳዱም ፡ ለቀቃት ፤ ተነሥታም ፡ አገለገለቻቸው ።
፲፮፡፲፯ በመሸም ፡ ጊዜ ፡ አጋንንት ፡ ያደረባቸውን ፡ ብዙዎችን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አመጡ ፤ በነቢዩ ፡ በኢሳይያስ ፦ እርሱ ፡ ድካማችንን ፡ ተቀበለ ፡ ደዌያችንንም ፡ ተሸከመ ፡ የተባለው ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፤ መናፍስትን ፡ በቃሉ ፡ አወጣ ፥ የታመሙትንም ፡ ሁሉ ፡ ፈወሰ ።
፲፰ ኢየሱስም ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ሲከተሉት ፡ አይቶ ፡ ወደ ፡ ማዶ ፡ እንዲሻገሩ ፡ አዘዘ ።
፲፱ አንድ ፡ ጻፊም ፡ ቀርቦ ፦ መምህር ፡ ሆይ ፥ ወደምትሄድበት ፡ ሁሉ ፡ እከተልሃለሁ ፡ አለው ።
፳ ኢየሱስም ፦ ለቀበሮዎች ፡ ጕድጓድ ፡ ለሰማይም ፡ ወፎች ፡ መሳፈሪያ ፡ አላቸው ፥ ለሰው ፡ ልጅ ፡ ግን ፡ ራሱን ፡ የሚያስጠጋበት ፡ የለውም ፡ አለው ።
፳፩ ከደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ሌላው ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ አስቀድሜ ፡ እንድሄድ ፡ አባቴን ፡ እንድቀብር ፡ ፍቀድልኝ ፡ አለው ።
፳፪ ኢየሱስም ፦ ተከተለኝ ፥ ሙታናቸውንም ፡ እንዲቀብሩ ፡ ሙታንን ፡ ተዋቸው ፡ አለው ።
፳፫ ወደ ፡ ታንኳም ፡ ሲገባ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ተከተሉት ።
፳፬ እነሆም ፥ ማዕበሉ ፡ ታንኳይቱን ፡ እስኪደፍናት ፡ ድረስ ፡ በባሕር ፡ ታላቅ ፡ መናወጥ ፡ ሆነ ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ።
፳፭ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ቀርበው ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ አድነን ፥ ጠፋን ፡ እያሉ ፡ አስነሡት ።
፳፮ እርሱም ፦ እናንተ ፡ እምነት ፡ የጎደላችሁ ፥ ስለ ፡ ምን ፡ ትፈራላችሁ ? አላቸው ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ተነሥቶ ፡ ነፋሱንና ፡ ባሕሩን ፡ ገሠጸ ፥ ታላቅ ፡ ጸጥታም ፡ ሆነ ።
፳፯ ሰዎቹም ፦ ነፋሳትና ፡ ባሕርስ ፡ ስንኳ ፡ የሚታዘዙለት ፥ ይህ ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ነው ? እያሉ ፡ ተደነቁ ።
፳፰ ወደ ፡ ማዶም ፡ ወደ ፡ ጌርጌሴኖን ፡ አገር ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፥ አጋንንት ፡ ያደሩባቸው ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ከመቃብር ፡ ወጥተው ፡ ተገናኙት ፤ እነርሱም ፡ ሰው ፡ በዚያ ፡ መንገድ ፡ ማለፍ ፡ እስኪሳነው ፡ ድረስ ፡ እጅግ ፡ ክፉዎች ፡ ነበሩ ።
፳፱ እነሆም ፦ ኢየሱስ ፡ ሆይ ፥ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፥ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አለን ? ጊዜው ፡ ሳይደርስ ፡ ልትሣቅየን ፡ ወደዚህ ፡ መጣህን ? እያሉ ፡ ጮኹ ።
፴ ከእነርሱም ፡ ርቆ ፡ የብዙ ፡ እሪያ ፡ መንጋ ፡ ይሰማራ ፡ ነበር ።
፴፩ አጋንንቱም ፦ ታወጣንስ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፥ ወደ ፡ እሪያው ፡ መንጋ ፡ ስደደን ፡ ብለው ፡ ለመኑት ።
፴፪ ሂዱ ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡ ወጥተው ፡ ወደ ፡ እሪያዎቹ ፡ ሄዱና ፡ ገቡ ፤ እነሆም ፥ የእሪያዎቹ ፡ መንጋ ፡ ሁሉ ፡ ከአፋፉ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ እየተጣደፉ ፡ ሮጡ ፡ በውኃም ፡ ውስጥ ፡ ሞቱ ።
፴፫ እረኞችም ፡ ሸሹ ፥ ወደ ፡ ከተማይቱም ፡ ሄደው ፡ ነገሩን ፡ ሁሉ ፡ አጋንንትም ፡ ያደሩባቸው ፡ የሆነውን ፡ አወሩ ።
፴፬ እነሆም ፥ ከተማው ፡ ሁሉ ፡ ኢየሱስን ፡ ሊገናኝ ፡ ወጣ ፥ ባዩትም ፡ ጊዜ ፡ ከአገራቸው ፡ እንዲሄድላቸው ፡ ለመኑት ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ በታንኳም ፡ ገብቶ ፡ ተሻገረና ፡ ወደ ፡ ገዛ ፡ ከተማው ፡ መጣ ።
፪ እነሆም ፥ በአልጋ ፡ የተኛ ፡ ሽባ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አመጡ ። ኢየሱስም ፡ እምነታቸውን ፡ አይቶ ፡ ሽባውን ፦ አንተ ፡ ልጅ ፥ አይዞህ ፥ ኃጢአትህ ፡ ተሰረየችልህ ፡ አለው ።
፫ እነሆም ፥ ከጻፎቹ ፡ አንዳንዱ ፡ በልባቸው ፦ ይህስ ፡ ይሳደባል ፡ አሉ ።
፬ ኢየሱስም ፡ አሳባቸውን ፡ አውቆ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ ስለ ፡ ምን ፡ በልባችሁ ፡ ክፉ ፡ ታስባላችሁ ?
፭ ኃጢአትህ ፡ ተሰረየችልህ ፡ ከማለት ፡ ወይስ ፦ ተነሣና ፡ ሂድ ፡ ከማለት ፡ ማናቸው ፡ ይቀላል ?
፮ ነገር ፡ ግን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ኃጢአትን ፡ ያስተሰርይ ፡ ዘንድ ፡ ለሰው ፡ ልጅ ፡ ሥልጣን ፡ እንዳለው ፡ እንድታውቁ ፥ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሽባውን ፦ ተነሣ ፤ አልጋህን ፡ ተሸከምና ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ ሂድ ፡ አለው ።
፯ ተነሥቶም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ።
፰ ሕዝቡም ፡ አይተው ፡ ተደነቁ ፥ ለሰውም ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ሥልጣን ፡ የሰጠ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አከበሩ ።
፱ ኢየሱስም ፡ ከዚያ ፡ አልፎ ፡ በመቅረጫው ፡ ተቀምጦ ፡ የነበረ ፡ ማቴዎስ ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ አየና ፦ ተከተለኝ ፡ አለው ። ተነሥቶም ፡ ተከተለው ።

፰ [illegible] ሉቃ. [illegible] ኢሳ. [illegible] ። [illegible] ዮሐ. [illegible] ። [illegible] ማር. [illegible] ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ኢሳ. [illegible] ። [illegible] ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ማር. [illegible] ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ዮሐ. [illegible] ማር. [illegible] ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ዮሐ. [illegible] ማር. [illegible] ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ዘሌዋ. [illegible] ። [illegible] ኢዮብ [illegible] ።

፱ [illegible] ማር. [illegible] ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ቆላ. [illegible] ማር. [illegible] ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ሉቃ. [illegible] ። [illegible] ማር. [illegible] ሉቃ. [illegible] ።

፲ በቤቱም ፡ በማዕድ ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፥ እነሆ ፥ ብዙ ፡ ቀራጮችና ፡ ኃጢአተኞች ፡ መጥተው ፡ ከኢየሱስና ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ጋር ፡ አብረው ፡
፲፩ ተቀመጡ ። ፈሪሳውያንም ፡ አይተው ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፦ መምህራችሁ ፡ ከቀራጮችና ፡ ከኃጢአተኞች ፡ ጋር ፡ አብሮ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይበ
፲፪ ላል ? አሉአቸው ። ኢየሱስም ፡ ሰምቶ ፦ ሕመ ምተኞች ፡ እንጂ ፡ ባለ ፡ ጤናዎች ፡ ባለ ፡ መድኃ
፲፫ ኒት ፡ አያስፈልጋቸውም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሄዳችሁ ፦ ምሕረትን ፡ እወዳለሁ ፡ መሥዋዕትንም ፡ አይደ ለም ፡ ያለው ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ተማሩ ፤ ኃጢ አተኞችን ፡ ወደ ፡ ንስሐ ፡ እንጂ ፡ ጻድቃንን ፡ ልጠራ ፡ አልመጣሁምና ፡ አላቸው ።

፲፬ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የዮሐንስ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀርበው ፦ እኛና ፡ ፈሪሳውያን ፥ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ የምንጦመው ፥ ደቀ ፡ መዛሙርትህ ፡ ግን ፡ የማይጦሙት ፡ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አሉት ።
፲፭ ኢየሱስም ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ ሚዜዎች ፡ ሙሽራው ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ሳለ ፡ ሊያዝኑ ፡ ይች ላሉን ? ነገር ፡ ግን ፡ ሙሽራው ፡ ከእነርሱ ፡ የሚ ወሰድበት ፡ ወራት ፡ ይመጣል ፥ በዚያ ፡ ጊዜም ፡
፲፮ ይጦማሉ ። ለአረጀ ፡ ልብስ ፡ አዲስ ፡ እራፊ ፡ የሚ ያኖር ፡ የለም ፤ መጣፊያው ፡ ልብሱን ፡ ይቦጭቀ
፲፯ ዋልና ፥ መቀደዱም ፡ የባሰ ፡ ይሆናል ። በአረጀ ፡ አቁማዳ ፡ አዲስ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ የሚያኖር ፡ የለም ፤ ቢደረግ ፡ ግን ፥ አቁማዳው ፡ ይፈነዳል ፥ የወይን ፡ ጠጁም ፡ ይፈስሳል ፡ አቁማዳውም ፡ ይጠ ፋል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አዲሱን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ በአ ዲስ ፡ አቁማዳ ፡ ያኖረዋል ፥ ሁለቱም ፡ ይጠበበ ቃሉ ።

፲፰ ይህንም ፡ ሲነግራቸው ፥ አንድ ፡ መኰንን ፡ መጥቶ ፦ ልጄ ፡ አሁን ፡ ሞተች ፤ ነገር ፡ ግን ፡ መጥተህ ፡ እጅህን ፡ ጫንባት ፥ በሕይወትም ፡ ትኖ
፲፱ ራለች ፡ እያለ ፡ ሰገደለት ። ኢየሱስም ፡ ተነሥቶ ፡
፳ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ጋር ፡ ተከተለው ። እነሆም ፥ ከአሥራ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ደም ፡ የሚ ፈስሳት ፡ ሴት ፡ በኋላው ፡ ቀርባ ፡ የልብሱን ፡
፳፩ ጫፍ ፡ ዳሰሰች ፤ በልብዋ ፦ ልብሱን ፡ ብቻ ፡ የዳሰስሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ እድናለሁ ፡ ትል ፡
፳፪ ነበረችና ። ኢየሱስም ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ አያ ትና ፦ ልጄ ፡ ሆይ ፥ አይዞሽ ፤ እምነትሽ ፡ አድኖ ሻል ፡ አላት ። ሴቲቱም ፡ ከዚያች ፡ ሰዓት ፡
፳፫ ጀምራ ፡ ዳነች ። ኢየሱስም ፡ ወደ ፡ መኰ ንኑ ፡ ቤት ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፥ አምቢልተኞች ንና ፡ የሚንጫጫውን ፡ ሕዝብ ፡ አይቶ ፦
፳፬ ብላቴናይቱ ፡ ተኝታለች ፡ እንጂ ፡ አልሞተ ችምና ፡ ፈቀቅ ፡ በሉ ፡ አላቸው ። በጣምም ፡
፳፭ ሳቁበት ። ሕዝቡን ፡ ግን ፡ ከአስወጡ ፡ በኋላ ፡ ገብቶ ፡ እጅዋን ፡ ያዘት ፥ ብላቴናይቱም ፡ ተነሣች ።
፳፮ ይም ፡ ዝና ፡ ወደዚያ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ወጣ ።
፳፯ ኢየሱስም ፡ ከዚያ ፡ ሲያልፍ ፡ ሁለት ፡ ዕው ሮች ፦ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ማረን ፡ ብለው ፡
፳፰ እየጮሁ ፡ ተከተሉት ። ወደ ፡ ቤትም ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ዕውሮቹ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀረቡ ፥ ኢየሱ ስም ፦ ይህን ፡ ማድረግ ፡ እንድችል ፡ ታምናላ ችሁን ? አላቸው ። አዎን ፥ ጌታ ፡ ሆይ ፡ አሉት ።
፳፱ በዚያን ፡ ጊዜ ፦ እንደ ፡ እምነታችሁ ፡ ይሁንላ
፴ ችሁ ፡ ብሎ ፡ ዓይኖቻቸውን ፡ ዳሰሰ ። ዓይኖቻቸ ውም ፡ ተከፈቱ ። ኢየሱስም ፦ ማንም ፡ እንዳ ያውቅ ፡ ተጠንቀቁ ፡ ብሎ ፡ በብርቱ ፡ አዘዛቸው ።
፴፩ እነርሱ ፡ ግን ፡ ወጥተው ፡ በዚያ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ አወሩ ።

፴፪ እነርሱም ፡ ሲወጡ ፥ እነሆ ፥ ጋኔን ፡ ያደረበ
፴፫ ትን ፡ ዲዳ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አመጡ ። ጋኔ ኑንም ፡ ካወጣው ፡ በኋላ ፡ ዲዳው ፡ ተናገረ ። ሕዝቡም ፦ እንዲህ ፡ ያለ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡
፴፬ ከቶ ፡ አልታየም ፡ እያሉ ፡ ተደነቁ ። ፈሪሳውያን ፡ ግን ፦ በአጋንንት ፡ አለቃ ፡ አጋንንትን ፡ ያወ ጣል ፡ አሉ ።

፴፭ ኢየሱስም ፡ በምኵራቦቻቸው ፡ እያስተማረ ፥ የመንግሥትንም ፡ ወንጌል ፡ እየሰበከ ፥ በሕዝ ብም ፡ ያለውን ፡ ደዌና ፡ ሕማም ፡ ሁሉ ፡ እየፈወሰ ፥ በከተማዎችና ፡ በመንደሮች ፡ ሁሉ ፡ ይዞር ፡ ነበር ።
፴፮ ብዙ ፡ ሕዝብም ፡ በየ ፡ ጊዜ ፥ እረኛ ፡ እንደ ፡ ሌላ ቸው ፡ በጎች ፡ ተጨንቀው ፡ ተጥለውም ፡ ነበ
፴፯ ርና ፡ አዘነላቸው ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛ ሙርቱን ፦ መከሩስ ፡ ብዙ ፡ ነው ፥ ሠራተኞች ፡
፴፰ ግን ፡ ጥቂቶች ፡ ናቸው ፤ እንግዲህ ፡ የመከሩን ፡ ጌታ ፡ ወደ ፡ መከሩ ፡ ሠራተኞች ፡ እንዲልክ ፡ ለም ኑት ፡ አላቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ አሥራ ፡ ሁለቱን ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ጠርቶ ፥ እንዲያወጡአቸው ፡ በርኵሳን ፡ መናፍስት ፡ ላይ ፡ ደዌንና ፡ ሕማምንም ፡ ሁሉ ፡
፪ እንዲፈውሱ ፡ ሥልጣን ፡ ሰጣቸው ። የአሥራ ፡ ሁለቱም ፡ ሐዋርያት ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ መጀ መሪያው ፡ ጴጥሮስ ፡ የተባለው ፡ ስምዖን ፡ ወን ድሙ ፡ እንድርያስም ፥ የዘብዴዎስ ፡ ልጅ ፡ ያዕ
፫ ቆብም ፡ ወንድሙ ፡ ዮሐንስም ፥ ፊልጶስም ፡ በር ተሎሜዎስም ፥ ቶማስም ፡ ቀራጩ ፡ ማቴዎስም ፥ የእልፍዮስ ፡ ልጅ ፡ ያዕቆብም ፡ ታዴዎስም ፡
፬ የተባለው ፡ ልብድዮስ ፥ ቀነናዊውም ፡ ስምዖን ፡ ይሁዳም ፡ አሳልፎ ፡ የሰጠው ፡ የአስቆሮቱ ፡ ይሁዳ ።
፭ እነዚህን ፡ አሥራ ፡ ሁለቱን ፡ ኢየሱስ ፡ ላካ ቸው ፥ አዘዛቸውም ፥ እንዲህም ፡ አለ ፦ በአሕ ዛብ ፡ መንገድ ፡ አትሂዱ ፥ ወደ ፡ ሰምራውያንም ፡

፱ ፲፫ ፤ ሆሴ. ፮፥፮ ፤ ማቴ. ፲፪፥፯ ፤ ፲፰፥፲፩ ። ፲፰—፳፮ ፤ ማር. ፭፥፳፪—፵፫ ፤ ሉቃ. ፰፥፵፩—፶፮ ። ፳ ፤ ዘሌ. ፲፭፥፳፭ ፤ ማር. ፫፥፲ ። ፳፯ ፤ ቍ. ፱ ። ፳፰ ፤ ምዕ. ፲፬፥፴፩ ። ፴ ፤ ምዕ. ፰፥፬ ። ፴፬ ፤ ምዕ. ፲፪፥፳፬ ፤ ማር. ፫፥፳፪ ፤ ሉቃ. ፲፩፥፲፭ ። ፴፭ ፤ ምዕ. ፬፥፳፫ ። ፴፮ ፤ ማር. ፮፥፴፬ ፤ ሕዝ. ፴፬፥፭ ። ፴፰ ፤ ሉቃ. ፲፥፪ ፤ ዮሐ. ፬፥፴፭ ።

፲ ፩ ፤ ማር. ፫፥፲፬ ፡ ፲፭ ፤ ሉቃ. ፱፥፩ ፡ ፪ ። ፪—፬ ፤ ምዕ. ፬፥፲፰ ፡ ፳፩ ፤ ፲፯፥፲፰ ፤ ዮሐ. ፩፥፵፪ ፤ ማር. ፫፥፲፮—፲፱ ፤ ሉቃ. ፮፥፲፬—፲፮ ፤ የሐዋ. ፩፥፲፫ ። ፭ ፤ ማር. ፮፥፯ ፤ ሉቃ. ፱፥፪ ።

፮ ከተማ፡ አትግቡ፤ ይልቅስ፡ የእስራኤል፡ ቤት፡ ወደሚሆኑ፡ ወደ፡ ጠፉት፡ በጎች፡ ሂዱ፡ እንጂ ።
፯ ሄዳችሁም ፥— መንግሥተ፡ ሰማያት፡ ቀርባለች፡
፰ ብላችሁ፡ ስበኩ ። ድውዮችን፡ ፈውሱ፤ሙታ ንን፡ አስነሡ፤ ለምጻሞችን፡ አንጹ፤ አጋንን ትን፡ አውጡ፤ በከንቱ፡ ተቀበላችሁ ፥ በከንቱ፡
፱ ስጡ ። ወርቅ፡ ወይም፡ ብር፡ ወይም፡ ናስ፡ በመ
፲ ቀነታችሁ ፥ ወይም ፡ ለመንገድ ፡ ከረጢት ፡ ወይም፡ ሁለት፡ እጀ፡ ጠባብ፡ ወይም፡ ጫማ፡ ወይም፡ በትር፡ አታግኙ፤ ለሠራተኛ፡ ምግቡ፡
፲፩ ይገባዋልና ። በምትገቡበትም፡ በማናቸይቱም፡ ከተማ፡ ወይም፡ መንደር ፥ በዚያ፡ የሚገባው፡ ማን፡ እንደ፡ ሆነ፡ በጥንቃቄ፡ መርምሩ፤ እስክት
፲፪ ወጡም ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ ተቀመጡ ። ወደ ፡
፲፫ ቤትም፡ ስትገቡ፡ ሰላምታ፡ ስጡ፤ ቤቱም፡ የሚ ገባው፡ ቢሆን፡ ሰላማችሁ፡ ይድረስለት፤ በይገ
፲፬ ባው፡ ግን፡ ሰላማችሁ፡ ይመለስላችሁ ። ከማይ ቀበላችሁም፡ ቃላችሁንም፡ ከማይሰሙ፡ ሁሉ ፥ ከዚያ፡ ቤት፡ ወይም ፡ ከዚያች ፡ ከተማ፡ ስት
፲፭ ወጡ፡ የእግራችሁን፡ ትቢያ፡ አራግፉ ። እው ነት፡ እላችኋለሁ ፥ በፍርድ ፡ ቀን ፡ ከዚያች ፡ ከተማ፡ ይልቅ፡ ለሰዶምና፡ ለገሞራ፡ አገር፡ ይቀ ልላቸዋል ።
፲፮ እነሆ ፥ እኔ ፡ እንደ ፡ በጎች ፡ በተኵላዎች ፡ መካከል፡ እልካችኋለሁ፤ ስለዚህ፡ እንደ፡ እባብ፡ ልባሞች ፡ እንደ ፡ ርግብም ፡ የዋሆች ፡ ሁኑ ።
፲፯ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ሸንጎ፡ አሳልፈው ፡ ይሰጡአ ችኋል ፥ በምኵራቦቻቸውም፡ ይገርፉአችኋልና፡
፲፰ ከሰዎች ፡ ተጠበቁ፤ ለእነርሱና ፡ ለአሕዛብም፡ ምስክር፡ እንዲሆን ፥ ስለ፡ እኔ፡ ወደ፡ ገዥዎች፡
፲፱ ወደ ፡ ነገሥታትም ፡ ትወሰዳላችሁ ። አሳልፈ ውም ፡ ቢሰጡአችሁ ፥ የምትናገሩት፡ በዚያች፡ ሰዓት፡ ይሰጣችኋልና፡ እንዴት፡ ወይስ፡ ምን፡
፳ እንድትናገሩ፡ አትጨነቁ፤ በእናንተ፡ የሚናገር፡ የአባታችሁ ፡ መንፈስ፡ ነው፡ እንጂ ፥ የምትና
፳፩ ገሩ፡ እናንተ፡ አይደላችሁምና ። ወንድምም ፡ ወንድሙን፡ አባትም፡ ልጁን፡ ለሞት፡ አሳልፎ፡ ይሰጣል ፥ ልጆችም፡ በወላጆቻቸው፡ ላይ፡ ይነ
፳፪ ሣሉ፡ ይገድሉአቸውማል ። በሁሉም፡ ስለ፡ ስሜ፡ የተጠላችሁ፡ ትሆናላችሁ፤ እስከ፡ መጨረሻ፡
፳፫ የሚጸና፡ ግን፡ እርሱ፡ ይድናል ። በአንዲቱ፡ ከተማም ፡ መከራ ፡ ቢያሳዩአችሁ ፡ ወደ ፡ ሌላ ይቱ ፡ ሽሹ፤ እውነት፡ እላችኋለሁና ፥ የሰው፡ ልጅ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ የእስራኤልን ፡ ከተ ማዎች ፡ አትዘልቁም ።
፳፬ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ከመምህሩ ፥ በሪያም ፡ ከጌ
፳፭ ታው ፡ አይበልጥም ። ደቀ ፡ መዝሙር ፡ እንደ ፡ መምህሩ ፥ በሪያም ፡ እንደ ፡ ጌታው ፡ መሆኑ ፡ ይበ ቃዋል ። በለቤቱን ፡ ብዔል ፡ ዜቡል ፡ ካሉት ፥ ቤተ ፡ ሰዎቹንማ ፡ እንዴት ፡ አብዝተው ፡ አይሉአቸው !
፳፮ እንግዲህ ፡ አትፍሩአቸው፤ የማይገለጥ ፡ የተ ከደነ ፥ የማይታወቅም ፡ የተሰወረ ፡ ምንም ፡ የለ
፳፯ ምና ። በጨለማ ፡ የምነግራችሁን ፡ በብርሃን ፡ ተናገሩ፤ በጆሮም ፡ የምትሰሙትን ፡ በሰገነት ፡
፳፰ ላይ ፡ ስበኩ ። ሥጋንም ፡ የሚገድሉትን ፡ ነፍስን ፡ ግን ፡ መግደል ፡ የማይችላቸውን ፡ አትፍሩ፤ ይል ቁስ ፡ ነፍስንም ፡ ሥጋንም ፡ በገሃነም ፡ ሊያጠፋ ፡
፳፱ የሚቻለውን ፡ ፍሩ ። ሁለት ፡ ድንቢጦች ፡ በአ ምስት ፡ ሳንቲም ፡ ይሸጡ ፡ የለምን ? ከእነርሱም ፡ አንዲቱ ፡ ያለ ፡ አባታችሁ ፡ ፈቃድ ፡ በምድር ፡
፴ ላይ ፡ አትወድቅም ። የእናንተስ ፡ የራሳችሁ ፡
፴፩ ጠጉር ፡ ሁሉ ፡ እንኳ ፡ ተቈጥሮአል ። እንግዲህ ፡ አትፍሩ፤ ከብዙ ፡ ድንቢጦች ፡ እናንተ ፡ ትበል
፴፪ ጣላችሁ ። ስለዚህ ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ ለሚመሰክር ልኝ ፡ ሁሉ ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ በሰማያት ፡ ባለው ፡
፴፫ በአባቴ ፡ ፊት ፡ እመሰክርለታለሁ፤ በሰው ፡ ፊትም ፡ የሚክደኝን ፡ ሁሉ ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ በሰ ማያት ፡ ባለው ፡ በአባቴ ፡ ፊት ፡ እክደዋለሁ ።
፴፬ በምድር ፡ ላይ ፡ ሰላምን ፡ ለማምጣት ፡ የመ ጣሁ ፡ አይምሰላችሁ፤ ሰይፍን ፡ እንጂ ፡ ሰላምን ፡
፴፭ ለማምጣት ፡ አልመጣሁም ። ሰውን ፡ ከአባቱ ፥ ሴት ፡ ልጅንም ፡ ከእናትዋ ፥ ምራትንም ፡ ከአማ
፴፮ ትዋ ፡ እለያይ ፡ ዘንድ ፡ መጥቻለሁና፤ ለሰውም ፡
፴፯ ቤተ ፡ ሰዎቹ ፡ ጠላቶች ፡ ይሆኑበታል ። ከእኔ ፡ ይልቅ ፡ አባቱን ፡ ወይም ፡ እናቱን ፡ የሚወድ ፡ ለእኔ ፡ ሊሆን ፡ አይገባውም፤ ከእኔ ፡ ይልቅም ፡ ወንድ ፡ ልጁን ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ልጁን ፡ የሚወድ ፡
፴፰ ለእኔ ፡ ሊሆን ፡ አይገባውም፤ መስቀሉንም ፡ የማ ይዝ ፡ በኋላዬም ፡ የማይከተለኝ ፡ ለእኔ ፡ ሊሆን ፡
፴፱ አይገባውም ። ነፍሱን ፡ የሚያገኝ ፡ ያጠፋታል ፥ ነፍሱንም ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ የሚያጠፋ ፡ ያገኛታል ።
፵ እናንተን ፡ የሚቀበል ፡ እኔን ፡ ይቀበላል ፥ እኔ
፵፩ ንም ፡ የሚቀበል ፡ የላከኝን ፡ ይቀበላል ። ነቢ ይን ፡ በነቢይ ፡ ስም ፡ የሚቀበል ፡ የነቢይን ፡ ዋጋ ፡ ይወስዳል ፥ ጻድቅንም ፡ በጻድቅ ፡ ስም ፡ የሚቀ
፵፪ በል ፡ የጻድቁን ፡ ዋጋ ፡ ይወስዳል ። ማንም ፡ ከእነ ዚህ ፡ ከታናናሾቹ ፡ ለአንዱ ፡ ቀዝቃዛ ፡ ጽዋ ፡ ውኃ ፡ ብቻ ፡ በደቀ ፡ መዝሙር ፡ ስም ፡ የሚያጠጣ ፥ እው ነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ዋጋው ፡ አይጠፋበትም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ኢየሱስም ፡ አሥራ ፡ ሁለቱን ፡ ደቀ ፡ መዛሙር ቱን ፡ ማዘዝ ፡ በፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ በከተሞቻቸው ፡ ሊያስተምርና ፡ ሊሰብክ ፡ ከዚያ ፡ አለፈ ።

፲ ። ፭ ፤ ም. ፫ ፥ ፪ ። ፱—፲፭ ፤ ማር. ፮ ፥ ፰—፲፩ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፫—፭ ፤ ፲ ፥ ፬—፲፪ ። ፲፭ ፤ ም. ፲፩ ፥ ፳፬ ። ፲፮ ፤ ሉቃ. ፲ ፥ ፫ ። ፲፯—፳፪ ፤ ማር. ፲፫ ፥ ፱—፲፫ ፤ ሉቃ. ፲፪ ፥ ፲፩ ፤ ፲፪ ፤ ፳፩ ፥ ፲፪—፲፱ ። ፳፪ ፤ ም. ፳፬ ፥ ፱ ፤ ፲፫ ። ፳፬ ፤ ሉቃ. ፮ ፥ ፵ ፤ ዮሐ. ፲፫ ፥ ፲፮ ፤ ፲፭ ፥ ፳ ። ፳፭ ፤ ማር. ፫ ፥ ፳፪ ። ፳፮—፴፫ ፤ ማር. ፬ ፥ ፳፪ ፤ ሉቃ. ፰ ፥ ፲፯ ፤ ፲፪ ፥ ፪—፱ ። ፴፬ ፤ ም. ፮ ፥ ፳፰ ። ፴፬ ፤ ፴፭ ፤ ሉቃ. ፲፪ ፥ ፶፩—፶፫ ። ፴፭ ፤ ሚክ. ፯ ፥ ፮ ። ፴፯ ፤ ሉቃ. ፲፬ ፥ ፳፮ ። ፴፰ ፤ ም. ፲፮ ፥ ፳፬ ፤ ማር. ፰ ፥ ፴፬ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፳፫ ፤ ፲፬ ፥ ፳፯ ። ፴፱ ፤ ም. ፲፮ ፥ ፳፭ ፤ ማር. ፰ ፥ ፴፭ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፳፬ ፤ ዮሐ. ፲፪ ፥ ፳፭ ። ፵ ፤ ም. ፲፰ ፥ ፭ ፤ ማር. ፱ ፥ ፴፯ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፵፰ ፤ ፲ ፥ ፲፮ ፤ ዮሐ. ፲፫ ፥ ፳ ። ፵፪ ፤ ም. ፳፭ ፥ ፵ ፤ ማር. ፱ ፥ ፵፩ ።

፪ ዮሐንስም ፡ በወህኒ ፡ ሳለ ፡ የክርስቶስን ፡ ሥራ ፡ ሰምቶ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ሁለት ፡ ላከና ፦ ፫ የሚመጣው ፡ አንተ ፡ ነህን ፡ ወይስ ፡ ሌላ ፡ እንጠብቅ ? አለው ፡፡ ፬ ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ ሄዳችሁ ፡ ያያችሁትን ፡ የሰማችሁትንም ፡ ለዮሐንስ ፡ አውሩለት ፤ ፭ ዕውሮች ፡ ያያሉ ፡ አንካሶችም ፡ ይሄዳሉ ፤ ለምጻሞችም ፡ ይነጻሉ ፡ ደንቆሮችም ፡ ይሰማሉ ፤ ሙታንም ፡ ይነሣሉ ፡ ለድሆችም ፡ ወንጌል ፡ ይሰበካል ፤ ፮ በእኔም ፡ የማይሰናከለው ፡ ሁሉ ፡ ብፁዕ ፡ ነው ፡፡

፯ እነዚያም ፡ ሲሄዱ ፡ ኢየሱስ ፡ ለሕዝቡ ፡ ስለ ፡ ዮሐንስ ፡ ሊናገር ፡ ጀመረ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦ ምን ፡ ልታዩ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወጣችሁ ? ፰ ነፋስ ፡ የሚወዘውዘውን ፡ ሸምበቆን ? ወይስ ፡ ምን ፡ ልታዩ ፡ ወጣችሁ ? ቀጭን ፡ ልብስ ፡ የለበሰ ፡ ሰውን ? እነሆ ፤ ቀጭን ፡ ልብስ ፡ የለበሱ ፡ በነገሥታት ፡ ቤት ፡ አሉ ፡፡ ፱ ወይስ ፡ ምን ፡ ልታዩ ፡ ወጣችሁ ? ነቢይን ? አዎን ፡ እላችኋለሁ ፤ ከነቢይም ፡ የሚበልጠውን ፡፡

፲ እነሆ ፤ መንገድህን ፡ በፊትህ ፡ የሚጠርግ ፡
መልክተኛዬን ፡ በፊትህ ፡ እልካለሁ ፡

፲፩ ተብሎ ፡ የተጻፈለት ፡ ይህ ፡ ነውና ፡፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፤ ከሴቶች ፡ ከተወለዱት ፡ መካከል ፡ ከመጥምቁ ፡ ዮሐንስ ፡ የሚበልጥ ፡ አልተነሣም ፤ በመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ግን ፡ ከሁሉ ፡ የሚያንሰው ፡ ይበልጠዋል ፡፡ ፲፪ ከመጥምቁም ፡ ከዮሐንስ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ትገፋለች ፤ ግፈኞችም ፡ ይናጠቋታል ፡፡ ፲፫ ነቢያት ፡ ሁሉና ፡ ሕጉ ፡ እስከ ፡ ዮሐንስ ፡ ድረስ ፡ ትንቢት ፡ ተናገሩ ፤ ፲፬ ልትቀበሉትስ ፡ ብትወዱ ፤ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡ ኤልያስ ፡ ይህ ፡ ነው ፡፡ ፲፭ የሚሰማ ፡ ጆሮ ፡ ያለው ፡ ይስማ ፡፡

፲፮ ነገር ፡ ግን ፡ ይህን ፡ ትውልድ ፡ በምን ፡ እመስለዋለሁ ? በገበያ ፡ የሚቀመጡትን ፡ ልጆች ፡ ይመስላሉ ፤ እነርሱም ፡ ባልንጀሮቻቸውን ፡ እየጠሩ ፦ ፲፯ እንቢልታ ፡ ነፋንላችሁ ፡ ዘፈንም ፡ አልዘፈናችሁም ፤ ሙሾ ፡ አወጣንላችሁ ፡ ዋይ ፡ ዋይም ፡ አላላችሁም ፡ ይሉአቸዋል ፡፡ ፲፰ ዮሐንስ ፡ ሳይበላና ፡ ሳይጠጣ ፡ መጣ ፤ እነርሱም ፦ ጋኔን ፡ አለበት ፡ አሉት ፡፡ ፲፱ የሰው ፡ ልጅ ፡ እየበላና ፡ እየጠጣ ፡ መጣ ፤ እነርሱም ፦ እነሆ ፤ በላተኛና ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ጠጭ ፤ የቀራጮችና ፡ የኃጢአተኞች ፡ ወዳጅ ፡ ይሉታል ፡፡ ጥበብም ፡ በልጆችዋ ፡ ጸደቀች ፡፡

፳ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የሚበዙ ፡ ተአምራት ፡ የተደረገባቸውን ፡ ከተማዎች ፡ ንስሐ ፡ ስላልገቡ ፡ ሊነቅፋቸው ፡ ጀመረ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦ ፳፩ ወዮልሽ ፡ ኮራዚ ፤ ወዮልሽ ፡ ቤተ ፡ ሳይዳ ፤ በእናንተ ፡ የተደረገው ፡ ተአምራት ፡ በጢሮስና ፡ በሲዶና ፡ ተደርጎ ፡ ቢሆን ፤ ማቅ ፡ ለብሰው ፡ አመድም ፡ ነስንሰው ፡ ከብዙ ፡ ጊዜ ፡ በፊት ፡ ንስሐ ፡ በገቡ ፡ ነበርና ፡፡ ፳፪ ነገር ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፤ በፍርድ ፡ ቀን ፡ ከእናንተ ፡ ይልቅ ፡ ለጢሮስና ፡ ለሲዶና ፡ ይቀልላቸዋል ፡፡ ፳፫ አንቺም ፡ ቅፍርናሆም ፤ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ከፍ ፡ አልሽን ? ወደ ፡ሲኦል ፡ ትወርጃለሽ ፤ በአንቺ ፡ የተደረገው ፡ ተአምራት ፡ በሰዶም ፡ ተደርጎ ፡ ቢሆን ፤ እስከ ፡ ዛሬ ፡ በኖረች ፡ ነበርና ፡፡ ፳፬ ነገር ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፤ በፍርድ ፡ ቀን ፡ ከአንቺ ፡ ይልቅ ፡ ለሰዶም ፡ አገር ፡ ይቀልላታል ፡፡

፳፭ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ኢየሱስ ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ አባት ፡ ሆይ ፤ የሰማይና ፡ የምድር ፡ ጌታ ፤ ይህን ፡ ከጥበበኞችና ፡ ከአስተዋዮች ፡ ሰውረህ ፡ ለሕፃናት ፡ ስለ ፡ ገለጥህላቸው ፡ አመሰግንሃለሁ ፤ ፳፮ አዎን ፤ አባት ፡ ሆይ ፤ ፈቃድህ ፡ በፊትህ ፡ እንዲህ ፡ ሆኖአልና ፡፡ ፳፯ ሁሉ ፡ ከአባቴ ፡ ዘንድ ፡ ተሰጥቶኛል ፤ ከአብ ፡ በቀር ፡ ወልድን ፡ የሚያውቅ ፡ የለም ፤ ከወልድም ፡ በቀር ፡ ወልድም ፡ ሊገልጥለት ፡ ከሚፈቅድ ፡ በቀር ፡ አብን ፡ የሚያውቅ ፡ የለም ፡፡ ፳፰ እናንተ ፡ ደካሞች ፡ ሸክማችሁ ፡ የከበደ ፡ ሁሉ ፤ ወደ ፡ እኔ ፡ ኑ ፤ እኔም ፡ አሳርፋችኋለሁ ፡፡ ፳፱ ቀንበሬን ፡ በላያችሁ ፡ ተሸከሙ ፡ ከእኔም ፡ ተማሩ ፤ እኔ ፡ የዋህ ፡ በልቤም ፡ ትሑት ፡ ነኝና ፤ ለነፍሳችሁም ፡ ዕረፍት ፡ ታገኛላችሁ ፤ ፴ ቀንበሬ ፡ ልዝብ ፡ ሸክሜም ፡ ቀሊል ፡ ነውና ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ፡፡

፩ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ኢየሱስ ፡ በሰንበት ፡ ቀን ፡ በእርሻ ፡ መካከል ፡ አለፈ ፤ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ተራቡና ፡ እሸት ፡ ይቀጥፉ ፡ ይበሉም ፡ ጀመር ፡፡ ፪ ፈሪሳውያንም ፡ አይተው ፦ እነሆ ፤ ደቀ ፡ መዛሙርትህ ፡ በሰንበት ፡ ማድረግ ፡ ያልተፈቀደውን ፡ ያደርጋሉ ፡ አሉት ፡፡ ፫ እርሱ ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ ዳዊትና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ በተራቡ ፡ ጊዜ ፤ እርሱ ፡ ያደረገውን ፤ ፬ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ገባ ፡ ከህናትም ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ እርሱና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ ሊበሉት ፡ ያልተፈቀደውን ፡ የመሥዋዕቱን ፡ ኅብስት ፡ እንደ ፡ በላ ፡ አላነበባችሁምን ? ፭ ካህናትም ፡ በሰንበት ፡ በመቅደስ ፡ ሰንበትን ፡ እንዲያረክሱ ፡ ኃጢአትም ፡ እንዳይሆንባቸው ፡ በሕጉ ፡ አላነበባችሁምን ? ፮ ነገር ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፤ ከመቅደስ ፡ የሚበልጥ ፡ ከዚህ ፡ አለ ፡፡ ፯ ምሕረትን ፡ እወዳለሁ ፡ መሥዋዕትንም ፡ አይደለም ፡ ያለው ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ብታውቁስ ፡ ኃጢአት ፡ የሌለባቸውን ፡ ባል

፲፩ ፡፡ ፪—፲፱ ፤ ሉቃ. ፯ ፤ ፲፰—፴፭ ፡፡ ፪ ፤ ምዕ. ፲፬ ፤ ፫ ፡፡ ፫ ፤ ዘዳግ. ፲፰ ፤ ፲፭ ፤ ዮሐ. ፮ ፤ ፲፬ ፡፡ ፭ ፤ ኢሳ. ፴፭ ፤ ፭ ፣ ፮ ፤ ፷፩ ፤ ፩ ፡፡ ፮ ፤ ምዕ. ፲፫ ፤ ፶፯ ፤ ፳፮ ፤ ፴፩ ፡፡ ፯ ፤ ምዕ. ፫ ፤ ፩ ፤ ፭ ፡፡ ፱ ፤ ምዕ. ፲፬ ፤ ፭ ፤ ፳፩ ፤ ፳፮ ፤ ሉቃ. ፩ ፤ ፸፮ ፡፡ ፲ ፤ ሚል. ፫ ፤ ፩ ፤ ማር. ፩ ፤ ፪ ፡፡ ፲፫ ፤ ሉቃ. ፲፮ ፤ ፲፮ ፡፡ ፲፬ ፤ ምዕ. ፲፯ ፤ ፲—፲፫ ፤ ሚል. ፬ ፤ ፭ ፡፡ ፲፭ ፤ ምዕ. ፲፫ ፤ ፱ ፤ ሉቃ. ፰ ፤ ፰ ፡፡ ፲፱ ፤ ምዕ. ፱ ፤ ፲ ፤ ዮሐ. ፱ ፤ ፬ ፡፡ ፳፩—፳፬ ፤ ሉቃ. ፲ ፤ ፲፪—፲፭ ፡፡ ፳፫ ፤ ኢሳ. ፲፬ ፤ ፲፫—፲፭ ፡፡ ፳፬ ፤ ምዕ. ፲ ፤ ፲፭ ፡፡ ፳፭—፳፯ ፤ ሉቃ. ፲ ፤ ፳፩ ፤ ፳፪ ፡፡ ፳፯ ፤ ምዕ. ፳፰ ፤ ፲፰ ፤ ዮሐ. ፫ ፤ ፴፭ ፤ ፲ ፤ ፲፭ ፡፡ ፳፱ ፤ ኤር. ፮ ፤ ፲፮ ፤ ዮሐ. ፲፫ ፤ ፲፭ ፡፡

፲፪ ፡፡ ፩—፰ ፤ ማር. ፪ ፤ ፳፫—፳፰ ፤ ሉቃ. ፮ ፤ ፩—፭ ፤ ዘዳግ. ፳፫ ፤ ፳፭ ፡፡ ፪ ፤ ዘጸአ. ፳ ፤ ፰—፲ ፡፡ ፫ ፤ ፩ ሳሙ. ፳፩ ፤ ፩—፮ ፡፡ ፬ ፤ ዘሌዋ. [illegible] ፡፡ ፭ ፤ ዘኁል. [illegible] ፡፡ ፯ ፤ ምዕ. ፱ ፤ ፲፫ ፤ ሆሴ. ፮ ፤ ፮ ፡፡

፰ ኩነናችሁም ፡ ነበር ። የሰው ፡ ልጅ ፡ የሰንበት ፡ ጌታ ፡ ነውና ።

፱ ከዚያም ፡ አልፎ ፡ ወደ ፡ ምኵራባቸው ፡ ገባ ።
፲ እነሆም ፡ እጁ ፡ የሰለለች ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ይከሱ ትም ፡ ዘንድ ፡— በሰንበት ፡ መፈወስ ፡ ተፈቅዶ
፲፩ ልን ? ብለው ፡ ጠየቁት ። እርሱ ፡ ግን ፡— ከእ ናንተ ፡ አንድ ፡ በግ ፡ ያለው ፡ በሰንበት ፡ በጕድ ጓድ ፡ ቢወድቅበት ፥ ይዞ ፡ የማያወጣው ፡ ሰው ፡
፲፪ ማን ፡ ነው ? እንግዲህ ፡ ሰው ፡ ከበግ ፡ ይልቅ ፡ እንደምን ፡ አይበልጥም ፤ ስለዚህ ፡ በሰንበት ፡ መልካም ፡ መሥራት ፡ ተፈቅዶአል ፡ አላቸው ።
፲፫ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ሰውየውን ፡— እጅህን ፡ ዘርጋ ፡ አለው ። ዘረጋትም ፥ እንደ ፡ ሁለተኛይቱም ፡
፲፬ ደህና ፡ ሆነች ። ፈሪሳውያን ፡ ግን ፡ ወጥተው ፡ እንዴት ፡ አድርገው ፡ እንዲያጠፉት ፡ ተማከሩ በት ።

፲፭ ኢየሱስም ፡ አውቆ ፡ ከዚያ ፡ ፈቀቅ ፡ አለ ። ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ተከተሉት ፥ ሁሉንም ፡ ፈወሳ
፲፮ ቸው ፥ እንዳይገልጡትም ፡ አዘዛቸው ፤ ስለ ነቢዩ ፡ በኢሳይያስ ፡ የተባለው ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ እን ዲህ ፡ ሲል ፡—

፲፰ እነሆ ፡ የመረጥሁት ፡ ብላቴናዬ ፥ ነፍሴ ፡ ደስ ፡ የተሰኘችበት ፡ ወዳጄ ፤ መንፈሴን ፡ በእ ርሱ ፡ ላይ ፡ አኖራለሁ ፥ ፍርድንም ፡ ለአሕ
፲፱ ዛብ ፡ ያወራል ። አይከራከርም ፡ አይጮህ ምም ፥ ድምፁንም ፡ በአደባባይ ፡ የሚሰማ ፡
፳ የለም ። ፍርድን ፡ ድል ፡ በመንሣት ፡ እስኪ ያወጣ ፥ የተቀጠቀጠን ፡ ሸምበቆ ፡ አይሰብ ርም ፡ የሚጤስን ፡ የጥዋፍ ፡ ክርም ፡ አያጠ
፳፩ ፋም ። አሕዛብም ፡ በስሙ ፡ ተስፋ ፡ ያደ ርጋሉ ።

፳፪ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ጋኔን ፡ ያደረበትን ፡ዕውር ፡ ዲዳም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አመጡ ፤ ዕውሩም ፡ ዲዳ ውም ፡ እስኪያይና ፡ እስኪናገር ፡ ድረስ ፡ ፈወ
፳፫ ሰው ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ቀገረሙና ፡— እንጃ ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ ይሆንን ? አሉ ።
፳፬ ፈሪሳውያን ፡ ግን ፡ሰምተው ፡— ይህ ፡ በብዔል ፡ ዜቡል ፡ በአጋንንት ፡ አለቃ ፡ካልሆነ ፡ በቀር ፡ አጋ
፳፭ ንንትን ፡ አያወጣም ፡ አሉ ። ኢየሱስ ፡ ግን ፡ አሳ ባቸውን ፡ አውቆ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— እርስ ፡ በርስዋ ፡ የምትለያይ ፡ መንግሥት ፡ ሁሉ ፡ ትጠ ፋለች ፥ እርስ ፡ በርሱ ፡ የሚለያይ ፡ ከተማም ፡
፳፮ ሁሉ ፡ ወይም ፡ ቤት ፡ አይቆምም ። ሰይጣንም ፡ ሰይጣንን ፡ የሚያወጣ ፡ ከሆነ ፥ እርስ ፡ በርሱ ፡ ተለያየ ፥ እንግዲህ ፡ መንግሥቱ ፡ እንዴት ፡ ትቆ
፳፯ ማለች ? እኔስ ፡ በብዔል ፡ ዜቡል ፡ አጋንንትን ፡ የማወጣ ፡ ከሆንሁ ፥ ልጆቻችሁ ፡ በማን ፡ ያወጡ አቸዋል ? ስለዚህ ፡ እነርሱ ፡ ፈራጆች ፡ ይሆኑባች

፳፰ ኋል ። እኔ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ አጋንንትን ፡ የማወጣ ፡ ከሆንሁ ፥ እንግዲህ ፡ የእ ግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ደርሳ
፳፱ ለች ። ወይስ ፡ ሰው ፡ አስቀድሞ ፡ ኃይለኛውን ፡ ሳያስር ፡ ወደ ፡ ኃይለኛው ፡ ቤት ፡ ገብቶ ፡ እቃ ውን ፡ ሊነጥቀው ፡ እንዴት ፡ ይችላል ? ከዚያም ፡
፴ ወዲያ ፡ ቤቱን ፡ ይበዘብዛል ። ከእኔ ፡ ጋር ፡ ያል ሆነ ፡ ይቃወመኛል ፥ ከእኔ ፡ ጋርም ፡ የማያከማች ፡
፴፩ ይበትናል ። ስለዚህ ፡ እላችኋለሁ ፥ ኃጢአትና ፡ ስድብ ፡ ሁሉ ፡ ለሰዎች ፡ ይሰረይላቸዋል ፥ ነገር ፡ ግን ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ በሰደበ ፡ አይሰረይለ
፴፪ ትም ። በሰው ፡ ልጅ ፡ ላይ ፡ ቃል ፡ የሚናገር ፡ ሁሉ ፡ ይሰረይለታል ፤ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ላይ ፡ ግን ፡ የሚናገር ፡ ሁሉ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ በሚመጣው ፡ አይሰረይለትም ።

፴፫ ዛፍ ፡ ከፍሬዋ ፡ ትታወቃለችና ፡ ዛፍዋን ፡ መልካም ፥ ፍሬዋንም ፡ መልካም ፡ አድርጉ ፥ ወይም ፡ ዛፍዋን ፡ ክፉ ፡ ፍሬዋንም ፡ ክፉ ፡ አድ
፴፬ ርጉ ። እናንተ ፡ የእፉኝት ፡ ልጆች ፥ ክፉዎች ፡ ስት ሆኑ ፡ መልካም ፡ ለመናገር ፡ እንዴት ፡ ትችላላ ችሁ ? በልብ ፡ ሞልቶ ፡ ከተረፈው ፡ አፍ ፡ ይናገራ
፴፭ ልና ። መልካም ፡ ሰው ፡ ከልቡ ፡ መልካም ፡ መዝ ገብ ፡ መልካም ፡ ነገርን ፡ ያወጣል ፥ ክፉ ፡ ሰውም ፡
፴፮ ከክፉ ፡ መዝገብ ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ያወጣል ። እኔ ፡ እላችኋለሁ ፥ ሰዎች ፡ ስለሚናገሩት ፡ ስለ ፡ ከንቱ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በፍርድ ፡ ቀን ፡ መልስ ፡ ይሰጡበ
፴፯ ታል ፤ ከቃልህ ፡ የተነሣ ፡ ትጸድቃለህና ፡ ከቃ ልህም ፡ የተነሣ ፡ ትኰነናለህ ።

፴፰ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከጻፎችና ፡ ከፈሪሳውያን ፡ አን ዳንዶቹ ፡ መለሱና ፡— መምህር ፡ ሆይ ፥ ከአንተ ፡
፴፱ ምልክት ፡ እንድናይ ፡ እንወዳለን ፡ አሉ ። እርሱ ፡ ግን ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— ክፉና ፡ አመን ዝራ ፡ ትውልድ ፡ ምልክት ፡ ይሻል ፥ ከነቢዩም ፡ ከዮ ናስ ፡ ምልክት ፡ በቀር ፡ ምልክት ፡ አይሰጠውም ።
፵ ዮናስ ፡ በዓሣ ፡ አንበሪ ፡ ሆድ ፡ ሦስት ፡ ቀንና ፡ ሦስት ፡ ሌሊት ፡ እንደ ፡ ነበረ ፥ እንዲሁ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በምድር ፡ ልብ ፡ ሦስት ፡ ቀንና ፡ ሦስት ፡ ሌሊት ፡
፵፩ ይኖራል ። የነነዌ ፡ ሰዎች ፡ በፍርድ ፡ ቀን ፡ ከዚህ ፡ ትውልድ ፡ ጋር ፡ ተነሥተው ፡ ይፈርዱበታል ፤ በዮናስ ፡ ስብከት ፡ ንስሐ ፡ ገብተዋልና ፥ እነሆም ፥
፵፪ ከዮናስ ፡ የሚበልጥ ፡ ከዚህ ፡ አለ ። ንግሥተ ፡ ዓዜብ ፡ በፍርድ ፡ ቀን ፡ ከዚህ ፡ ትውልድ ፡ ጋር ፡ ተነሥታ ፡ ትፈርድበታለች ፤ የሰሎሞንን ፡ ጥበብ ፡ ለመስማት ፡ ከምድር ፡ ዳር ፡ መጥታለችና ፥ እነ ሆም ፥ ከሰሎሞን ፡ የሚበልጥ ፡ ከዚህ ፡ አለ ።

፵፫ ርኩስ ፡ መንፈስ ፡ ግን ፡ ከሰው ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፥ ዕረፍት ፡ እየፈለገ ፡ ውኃ ፡ በሌለበት ፡ ቦታ ፡ ያል
፵፬ ፋል ፥ አያገኝምም ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡— ወደ ፡

፲፪። [illegible]

ወጣሁበት ፡ ቤቴ ፡ እመለሳለሁ ፡ ይላል ፤ ሲመ
ጣም ፡ ባዶ ፡ ሆኖ ፡ ተጠርጎና ፡ አጊጦ ፡ ያገኘ
፵፭ ዋል ። ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ይሄድና ፡ ከእርሱ ፡ የከፉ
ትን ፡ ሰበት ፡ ሌሎችን ፡ ኢጋንንት ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
ይወስዳል ፥ ገብተውም ፡ በዚያ ፡ ይኖራሉ ፤ ለዚ
ያም ፡ ሰው ፡ ከፊተኛው ፡ ይልቅ ፡ የኋለኛው ፡
ይብሰበታል ። ስዚህ ፡ ክፉ ፡ ትውልድ ፡ ደግሞ ፡
እንዲሁ ፡ ይሆንበታል ።

፵፮ ገናም ፡ ለሕዝቡ ፡ ሲናገር ፥ እነሆ ፡ እናቱና ፡
ወንድሞቹ ፡ ሊነጋገሩት ፡ ፈልገው ፡ በውጭ ፡
፵፯ ቆመው ፡ ነበር ። አንዱም ፦ እነሆ ፥ እናትህና ፡
ወንድሞችህ ፡ ሊነጋገሩህ ፡ ፈልገው ፡ በውጭ ፡
፵፰ ቆመዋል ፡ አለው ። እርሱ ፡ ግን ፡ ለነገረው ፡
መለሰ ፦ እናቴ ፡ ማን ፡ ናት ? ወንድሞቼስ ፡ እነ
፵፱ ማን ፡ ናቸው ? አለው ። እጁንም ፡ ወደ ፡ ደቀ ፡
መዛሙርቱ ፡ ዘርግቶ ፦ እነሆ ፡ እናቴና ፡ ወንድ
፶ ሞቼ ፤ በሰማያት ፡ ያለውን ፡ የአባቴን ፡ ፈቃድ ፡
የሚያደርግ ፡ ሁሉ ፥ እርሱ ፡ ወንድሜ ፡ እኅቴም ፡
እናቴም ፡ ነውና ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ በዚያን ፡ ቀን ፡ ኢየሱስ ፡ ከቤት ፡ ወጥቶ ፡ በባ
፪ ሕር ፡ አጠገብ ፡ ተቀመጠ ፤ እርሱም ፡ በታንኳ ፡
ገብቶ ፡ እስኪቀመጥ ፡ ድረስ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ወደ
እርሱ ፡ ተሰበሰቡ ፥ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በወደቡ ፡
፫ ቆመው ፡ ነበር ። በምሳሌም ፡ ብዙ ፡ ነገራቸው ፡
እንዲህም ፡ አላቸው ፦ እነሆ ፥ ዘሪ ፡ ሊዘራ ፡ወጣ ።
፬ እርሱም ፡ ሲዘራ ፡ አንዳንዱ ፡ በመንገድ ፡ ዳር ፡
፭ ወደቀ ፥ ወፎችም ፡ መጥተው ፡ በሉት ። ሌላ
ውም ፡ ብዙ ፡ መሬት ፡ በሌለበት ፡ በጭንጫ ፡
ላይ ፡ ወደቀ ፤ ጥልቅ ፡ መሬትም ፡ ስላልነበረው ፡
፮ ወዲያው ፡ በቀለ ፥ ፀሐይ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡
፯ ጠወለገ ፥ ሥርም ፡ ስላልነበረው ፡ ደረቀ ። ሌላ
ውም ፡ በእሾህ ፡ መካከል ፡ ወደቀ ፥ እሾህም ፡
፰ ወጣና ፡ አነቀው ። ሌላውም ፡ በመልካም ፡
መሬት ፡ ወደቀ ፤ አንዱም ፡ መቶ ፥ አንዱም ፡
፱ ስድሳ ፥ አንዱም ፡ ሠላሳ ፡ ፍሬ ፡ ሰጠ ። የሚሰማ ፡
ጆሮ ፡ ያለው ፡ ይስማ ።

፲ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ቀርበው ፦ ስለ ፡ ምን ፡
፲፩ በምሳሌ ፡ ትነግራቸዋለህ ? አሉት ። እርሱም ፡
መለሰ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ ለእናንተ ፡ የመን
ግሥተ ፡ ሰማያትን ፡ ምሥጢር ፡ ማወቅ ፡ ተሰጥ
ቶአችኋል ፥ ለእነርሱ ፡ ግን ፡ አልተሰጣቸውም ።
፲፪ ላለው ፡ ይሰጠዋልና ፡ ይበዛለትማል ፤ ከሌለው ፡
ግን ፡ ያው ፡ ያለው ፡ እንኳ ፡ ይወሰድበታል ።
፲፫ ስለዚህ ፡ እያዩ ፡ ስለማያዩ ፡ እየሰሙም ፡ ስለማ
ይሰሙ ፡ ስለማያስተውሉም ፡ በምሳሌ ፡ እነግራ
ቸዋለሁ ።

፲፬ መስማትን ፡ ትሰማላችሁና ፡ አታስተውሉም ፥
ማየትም ፡ ታያላችሁና ፡ አትመለከቱም ።
፲፭ በዓይናቸው ፡ እንዳያዩ ፥ በጆሮአቸውም ፡
እንዳይሰሙ ፥ በልባቸውም ፡ እንዳያስተ
ውሉ ፥ ተመልሰውም ፡ እንዳልፈውሳቸው ፥
የዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ልብ ፡ ደንድኖአልና ፡ ጆሮ
አቸውም ፡ ደንቁሮአል ፡ ዓይናቸውንም ፡
ጨፍነዋል ፡

የሚል ፡ የኢሳይያስ ፡ ትንቢት ፡ በእነርሱ ፡ ይፈጸ
፲፮ ማል ። የእናንተ ፡ ግን ፡ ዓይኖቻችሁ ፡ ስለሚያዩ ፡
ጆሮቻችሁም ፡ ስለሚሰሙ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ።
፲፯ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ብዙዎች ፡ ነቢያትና ፡ጻድ
ቃን ፡ የምታዩትን ፡ ሊያዩ ፡ ተመኝተው ፡ አላ
ዩም ፥ የምትሰሙትንም ፡ ሊሰሙ ፡ ተመኝተው ፡
አልሰሙም ።

፲፰ እንግዲህ ፡ እናንተ ፡ የዘሪውን ፡ ምሳሌ ፡ ስሙ ።
፲፱ የመንግሥትን ፡ ቃል ፡ ሰምቶ ፡ በማያስተውል ፡
ሁሉ ፥ ክፉው ፡ ይመጣል ፥ በልቡ ፡ የተዘራው
ንም ፡ ይነጥቃል ፤ በመንገድ ፡ ዳር ፡ የተዘራው ፡
፳ ይህ ፡ ነው ። በጭንጫ ፡ ላይ ፡ የተዘራውም ፡ ይህ ፡
ቃሉን ፡ ሰምቶ ፡ ወዲያው ፡ በደስታ ፡ የሚቀበ
፳፩ ለው ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለጊዜው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
በእርሱ ፡ ሥር ፡ የለውም ፥ ስቃሉ ፡ ምክንያትም ፡
መከራ ፡ ወይም ፡ ስደት ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ወዲያው ፡
፳፪ ይሰናከላል ። በእሾህ ፡ መካከል ፡ የተዘራውም ፡
ይህ ፡ ቃሉን ፡ የሚሰማ ፡ ነው ፥ የዚህም ፡ ዓለም ፡
አሳብና ፡ የባለጠግነት ፡ መታለል ፡ ቃሉን ፡ ያን
፳፫ ቃል ፥ የማያፈራም ፡ ይሆናል ። በመልካም ፡
መሬት ፡ የተዘራውም ፡ ይህ ፡ ቃሉን ፡ ሰምቶ ፡
የሚያስተውል ፡ ነው ፤ እርሱም ፡ ፍሬ ፡ ያፈራል ፡
አንዱም ፡ መቶ ፡ አንዱም ፡ ስድሳ ፡ አንዱም ፡
ሠላሳ ፡ ያደርጋል ።

፳፬ ሌላ ፡ ምሳሌ ፡ አቀረበላቸው ፡ እንዲህም ፡
አለ ፦ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ በእርሻው ፡ መል
፳፭ ካም ፡ ዘርን ፡ የዘራን ፡ ሰው ፡ ትመስላለች ። ሰዎቹ ፡
ሲተኙ ፡ ግን ፡ ጠላቱ ፡ መጣና ፡ በስንዴው ፡ መካ
፳፮ ከል ፡ እንክርዳድን ፡ ዘርቶ ፡ ሄደ ። ስንዴውም ፡
በበቀለና ፡ በአፈራ ፡ ጊዜ ፡ እንክርዳዱ ፡ ደግሞ ፡
፳፯ ያን ፡ ጊዜ ፡ ታየ ። የባለቤቱም ፡ ባሮች ፡ ቀር
በው ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ መልካምን ፡ ዘር ፡ በእርሻህ ፡
ዘርተህ ፡ አልነበርህምን ? እንክርዳዱንስ ፡ ከወ
፳፰ ዴት ፡ አገኘ ? አሉት ። እርሱም ፦ ጠላት ፡
ይህን ፡ አደረገ ፡ አላቸው ። ባሮቹም ፦ እንግ
ዲህ ፡ ሄደን ፡ ብንለቅመው ፡ ትወዳለህን ? አሉት ።
፳፱ እርሱ ፡ ግን ፦ እንክርዳዱን ፡ ስትለቅሙ ፡ ስን
ዴውን ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ እንዳትነቅሉት ፡ አይሆ
፴ ንም ። ተዉአቸው ፤ እስከ ፡ መከር ፡ ጊዜ ፡ አብ
ረው ፡ ይደጉ ፤ በመከር ፡ ጊዜም ፡ አጫጆችን ፦
እንክርዳዱን ፡ አስቀድማችሁ ፡ ልቀሙ ፡ በእሳ
ትም ፡ ለማቃጠል ፡ በየነዶው ፡ እሰሩ ፥ ስንዴ
ውን ፡ ግን ፡ በጎተራዬ ፡ ክተቱ ፡ እላለሁ ፡ አለ ።

፴፩ ሌላ ፡ ምሳሌ ፡ አቀረበላቸው ፡ እንዲህም ፡

፲፪ ። ፵፮—፶ ፤ ማር. ፫ ፥ ፴፩—፴፭ ፤ ሉቃ. ፰ ፥ ፲፱—፳፩ ፤ ማቴ. ፲፫ ፥ ፶፭ ።

፲፫ ። ፩—፳፫ ፤ ማር. ፬ ፥ ፩—፳ ፤ ሉቃ. ፰ ፥ ፬—፲፭ ። ፲፪ ፤ ማቴ. ፳፭ ፥ ፳፱ ፤ ማር. ፬ ፥ ፳፭ ፤ ሉቃ. ፰ ፥ ፲፰ ። ፲፫ ፤ [illegible] ፲፬—፲፭ ፤ ኢሳ. ፮ ፥ ፱ ፥ ፲ ። ፲፯ ፤ ሉቃ. ፲ ፥ ፳፬ ። [illegible] ፴፩ ፥ ፴፪ ፤ ማር. ፬ ፥ ፴—፴፪ ፤ ሉቃ. ፲፫ ፥ ፲፰ ፥ ፲፱ ።

አለ ፡— መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ሰው ፡ ወስዶ ፡ በእ
ርሻው ፡ የዘራትን ፡ የሰናፍጭ ፡ ቅንጣት ፡ ትመ
፴፪ ስላለች ፤ እርስዋም ፡ ከዘር ፡ ሁሉ ፡ ታንስለች ፥
በአደገች ፡ ጊዜ ፡ ግን ፥ ከአታክልቶች ፡ ትበል
ጣለች ፡ የሰማይም ፡ ወፎች ፡ መጥተው ፡ በቅርን
ጫፎችዋ ፡ እስኪሰፍሩ ፡ ድረስ ፡ ዛፍ ፡ ትሆናለች ።
፴፫ ሌላ ፡ ምሳሌ ፡ ነገራቸው ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—
መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ሁሉ ፡ እስኪቦካ ፡ ድረስ ፡
ሴት ፡ ወስዳ ፡ በሦስት ፡ መስፈሪያ ፡ ዱቄት ፡ የሸ
ሸገችውን ፡ እርሾ ፡ ትመስላለች ።

፴፬፡፴፭ ኢየሱስም ፡ ለሕዝቡ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ በምሳሌ ፡
ተናገረ ፤ በነቢዩም ፡—

> በምሳሌ ፡ አፌን ፡ እከፍታለሁ ፥ ዓለም ፡ ከተ
> ፈጠረ ፡ ጀምሮ ፡ የተሰወረውንም ፡ እናገራ
> ለሁ ፡

የተባለው ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ ያለ ፡ ምሳሌ ፡ አል
ተናገራቸውም ።

፴፮ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡን ፡ ትቶ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡
ገባ ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀር
በው ፡— የእርሻውን ፡ እንክርዳድ ፡ ምሳሌ ፡ ተር
፴፯ ጕምልን ፡ አሉት ። እርሱም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡
አላቸው ፡— መልካምን ፡ ዘር ፡ የዘራው ፡ የሰው ፡
፴፰ ልጅ ፡ ነው ፤ እርሻውም ፡ ዓለም ፡ ነው ፤ መልካ
ሙም ፡ ዘር ፡ የመንግሥት ፡ ልጆች ፡ ናቸው ፤
፴፱ እንክርዳዱም ፡ የክፉው ፡ ልጆች ፡ ናቸው ፥ የዘራ
ውም ፡ ጠላት ፡ ዲያብሎስ ፡ ነው ፤ መከሩም ፡ የዓ
ለም ፡ መጨረሻ ፡ ነው ፥ አጫጆችም ፡ መላእክት ፡
፵ ናቸው ። እንግዲህ ፡ እንክርዳድ ፡ ተለቅሞ ፡ በእ
ሳት ፡ እንደሚቃጠል ፥ በዓለም ፡ መጨረሻ ፡ እን
፵፩ ዲሁ ፡ ይሆናል ። የሰው ፡ ልጅ ፡ መላእክቱን ፡
ይልካል ፥ ከመንግሥቱም ፡ እንቅፋትን ፡ ሁሉ ፡
፵፪ ዓመፃንም ፡ የሚያደርጉትን ፡ ይለቅማሉ ፥ ወደ ፡
እቶን ፡ እሳትም ፡ ይጥሉአቸዋል ፤ በዚያ ፡ ልቅ
፵፫ ሶና ፡ ጥርስ ፡ ማፋጨት ፡ ይሆናል ። በዚያን ፡
ጊዜ ፡ ጻድቃን ፡ በአባታቸው ፡ መንግሥት ፡
እንደ ፡ ፀሐይ ፡ ይበራሉ ። የሚሰማ ፡ ጆሮ ፡
ያለው ፡ ይስማ ።

፵፬ ደግሞ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ በእርሻ ፡
ውስጥ ፡ የተሰወረን ፡ መዝገብ ፡ ትመስላለች ፤
ሰውም ፡ አግኝቶ ፡ሰወረው ፥ ከደስታውም ፡ የተ
ነሣ ፡ ሄዶ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ሸጠና ፡ ያን ፡ እርሻ ፡
ገዛ ።

፵፭ ደግሞ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ መልካምን ፡
፵፮ ዕንቍ ፡ የሚሻ ፡ ነጋዴን ፡ ትመስላለች ፤ ዋጋዋም ፡
እጅግ ፡ የበዛ ፡ አንዲት ፡ ዕንቍ ፡ ባገኘ ፡ ጊዜ ፡
ሄዶ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ሸጠና ፡ ገዛት ።

፵፯ ደግሞ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ የተ
ጣለች ፡ ከሁሉም ፡ ዓይነት ፡ የሰበሰበች ፡ መረብን ፡
፵፰ ትመስላለች ፤ በሞላችም ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ወደቡ ፡
አወጡአት ፥ ተቀምጠውም ፡ መልካሙን ፡ ለቅ
መው ፡ በዕቃዎች ፡ ውስጥ ፡ አከማቹ ፡ ክፉውን ፡
፵፱ ግን ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ጣሉት ። በዓለም ፡ መጨረሻ ፡
እንዲሁ ፡ ይሆናል ፤ መላእክት ፡ መጥተው ፡ ኃጢ
አተኞችን ፡ ከጻድቃን ፡ መካከል ፡ ይለዩአቸዋል ፥
፶ ወደ ፡ እቶን ፡ እሳትም ፡ ይጥሉአቸዋል ፤ በዚያ ፡
ልቅሶና ፡ ጥርስ ፡ ማፋጨት ፡ ይሆናል ።

፶፩ ኢየሱስም ፡— ይህን ፡ ሁሉ ፡ አስተዋላችሁን ?
፶፪ አላቸው ፤ አዎን ፡ አሉት ። እርሱም ፡— ስለዚህ ፡
የመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ የሆነ ፡
ጻፊ ፡ ሁሉ ፡ ከመዝገቡ ፡ አዲሱንና ፡ አሮጌውን ፡
የሚያወጣ ፡ ባለቤትን ፡ ይመስላል ፡ አላቸው ።

፶፫ ኢየሱስም ፡ እነዚህን ፡ ምሳሌዎች ፡ ከጨረሰ ፡
፶፬ በኋላ ፡ ከዚያ ፡ ሄደ ። ወደ ፡ ገዛ ፡ አገሩም ፡ መጥቶ ፡
እስኪገረሙ ፡ ድረስ ፡ በምኵራባቸው ፡ ያስተም
ራቸው ፡ ነበር ፤ እንዲህም ፡ አሉ ፡— ይህን ፡ ጥበ
ብና ፡ ተአምራት ፡ ይህ ፡ ከወዴት ፡ አገኘው ?
፶፭ ይህ ፡ የጸራቢ ፡ ልጅ ፡ አይደለምን ? እናቱስ ፡
ማርያም ፡ ትባል ፡ የለምን ? ወንድሞቹስ ፡ ያዕቆ
ብና ፡ ዮሴ ፡ ስምዖንም ፡ ይሁዳም ፡ አይደሉምን ?
፶፮ እኅቶቹስ ፡ ሁሉ ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ ያሉ ፡ አይደሉ
ምን ? እንኪያስ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ከወዴት ፡ አገ
፶፯ ኘው ? ተሰናከሉበትም ። ኢየሱስ ፡ ግን ፡— ነቢይ ፡
ከገዛ ፡ አገሩና ፡ ከገዛ ፡ ቤቱ ፡ በቀር ፡ ሳይከበር ፡
፶፰ አይቀርም ፡ አላቸው ። በአለማመናቸውም ፡ ምክ
ንያት ፡ በዚያ ፡ ብዙ ፡ ተአምራት ፡ አላደረገም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ በዚያ ፡ ዘመን ፡ የአራተኛው ፡ ክፍል ፡ ገዥ ፡
፪ ሄሮድስ ፡ የኢየሱስን ፡ ዝና ፡ ሰማ ፥ ለብላቴኖ
ቹም ፡— ይህ ፡ መጥምቁ ፡ ዮሐንስ ፡ ነው ፤ እርሱ ፡
ከሙታን ፡ ተነሥቶአል ፥ ስለዚህም ፡ ኃይል ፡
፫ በእርሱ ፡ ይደረጋል ፡ አለ ። ሄሮድስ ፡ በወን
ድሙ ፡ በፊልጶስ ፡ሚስት ፡ በሄሮድያዳ ፡ ምክን
ያት ፡ ዮሐንስን ፡ አስይዞ ፡ አሳስሮት ፡ በወህኒ ፡
፬ አኑሮት ፡ ነበርና ፤ ዮሐንስ ፡— እርስዋ ፡ ለአንተ ፡
ትሆን ፡ ዘንድ ፡ አልተፈቀደም ፡ ይለው ፡ ነበርና ።
፭ ሊገድለውም ፡ ወዶ ፡ ሳለ ፥ ሕዝቡ ፡ እንደ ፡ ነቢይ ፡
፮ ስለ ፡ አዩት ፡ ፈራቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ ሄሮድስ ፡
የተወለደበት ፡ ቀን ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፥ የሄሮድያዳ ፡
ልጅ ፡ በመካከላቸው ፡ ዘፈነች ፡ ሄሮድስንም ፡
፯ ደስ ፡ አሰኘችው ፤ ስለዚህም ፡ የምትለምነውን ፡
ሁሉ ፡ እንዲሰጣት ፡ በመሐላ ፡ ተስፋ ፡ አደረገ
፰ ላት ። እርስዋም ፡ በእናትዋ ፡ ተመክራ ፡— የመ
ጥምቁን ፡ የዮሐንስን ፡ ራስ ፡ በዚህ ፡ በወጭት ፡
፱ ስጠኝ ፡ አለችው ። ንጉሡም ፡ አዘነ ፥ ነገር ፡
ግን ፡ ስለ ፡ መሐላው ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ተቀም

፲፫ ። ፴፩ ፤ ሉቃ· ፲፫ ፡ ፲፰ ። ፴፪ ፤ ማር· ፬ ፥ ፴፩ ፤ ፴፬ ። ፴፭ ፤ መዝ· ፸፰ ፥ ፪ ። ፵፪ ፤ ም· ፰ ፥ ፲፪ ። ፵፫ ፤ ዳን· ፲፪ ፥ ፫ ።
፶፬—፶፰ ፤ ማር· ፮ ፥ ፩—፮ ፤ ሉቃ· ፬ ፥ ፲፮—፴ ። ፶፭ ፤ ም· ፲፪ ፥ ፵፮ ። ፶፯ ፤ ም· ፲፱ ፥ ፳፱ ። ፶፯ ፤ ዮሐ· ፬ ፥ ፵፬ ።
፶፰ ፤ ም· ፲፩ ፥ ፮ ፤ ዮሐ· ፬ ፥ ፵፬ ።

፲፬ ። ፩—፪ ፤ ማር· ፮ ፥ ፲፬—፲፮ ፤ ሉቃ· ፱ ፥ ፯—፱ ፤ ፫ ፥ ፲፱—፳ ። ፬ ፤ ዘሌዋ· ፲፰ ፥ ፲፮ ። ፭ ፤ ም· ፳፩ ፥ ፳፮ ፤ ማር· ፮ ፥ ፳፱ ፤ ፳ ።
፫—፲፪ ፤ ማር· ፮ ፥ ፲፯—፳፱ ።

ጠው ፡ ስላሉት ፡ ሰዎች ፡ እንዲሰጡአት ፡ ለዘዘ ፤
፲ ልኮም ፡ የዮሐንስን ፡ ራስ ፡ በወህኒ ፡ አስቆረ
፲፩ ጠው ። ራሱንም ፡ በወጭት ፡ አምጥተው ፡ ለብ
ላቴናይቱ ፡ ሰጡአት ፤ ወደ ፡ እናትዋም ፡ ወሰ
፲፪ ደችው ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ቀርበው ፡ በድ
ኑን ፡ ወሰዱና ፡ ቀበሩት ፤ መጥተውም ፡ ለኢየ
ሱስ ፡ አወሩለት ።

፲፫ ኢየሱስም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ከዚያ ፡ ብቻውን ፡
ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በታንኳ ፡ ፈቀቅ ፡ አለ ፤ ሕዝ
ቡም ፡ ሰምተው ፡ ከከተማዎቹ ፡ በእግር ፡ ተከተ
፲፬ ሉት ። ወጥቶም ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ አየና ፡ አዘነላ
፲፭ ቸው ፡ ድውዮቻቸውንም ፡ ፈወሰ ። በመሸም ፡
ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀርበው ፡—
ቦታው ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ነው ፡ አሁንም ፡ ሰዓቱ ፡
አልፎአል ፤ ወደ ፡ መንደሮች ፡ ሄደው ፡ ለራሳ
ቸው ፡ ምግብ ፡ እንዲገዙ ፡ ሕዝቡን ፡ አሰናብት ፡
፲፮ አሉት ። ኢየሱስም ፡— እናንተ ፡ የሚበሉትን ፡
ስጡአቸው ፡ እንጂ ፡ ሊሄዱ ፡ አያስፈልግም ፡
፲፯ አላቸው ። እነርሱም ፡— ከአምስት ፡ እንጀራና ፡
ከሁለት ፡ ዓሣ ፡ በቀር ፡ በዚህ ፡ የለንም ፡ አሉት ።
፲፰ እርሱም ፡— እነዚያን ፡ ወደዚህ ፡ አምጡልኝ ፡
፲፱ አላቸው ። ሕዝቡም ፡ በሣር ፡ ላይ ፡ እንዲቀ
መጡ ፡ አዘዘ ፤ አምስቱንም ፡ እንጀራና ፡ ሁለ
ቱን ፡ ዓሣ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አሻቅቦ ፡ አየና ፡
ባረከ ፤ እንጀራውንም ፡ ቈርሶ ፡ ለደቀ ፡ መዛሙ
ርቱ ፡ ሰጠ ፤ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ለሕዝቡ ።
፳ ሁሉም ፡ በልተው ፡ ጠገቡ ፤ የተረፈውንም ፡
ቍርስራሽ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ መሶብ ፡ ሙሉ ፡
፳፩ አነሡ ። ከሴቶችና ፡ ከልጆችም ፡ በቀር ፡ የበ
ሉት ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ወንዶች ፡ ያህሉ ፡ ነበር ።

፳፪ ወዲያውም ፡ ሕዝቡን ፡ ሲያሰናብት ፡ ሳለ ፤
ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ በታንኳይቱ ፡ ገብተው ፡ ወደ ፡
፳፫ ማዶ ፡ እንዲቀድሙት ፡ ግድ ፡ አላቸው ። ሕዝ
ቡንም ፡ አሰናብቶ ፡ ይጸልይ ፡ ዘንድ ፡ ብቻውን ፡
ወደ ፡ ተራራ ፡ ወጣ ። በመሸም ፡ ጊዜ ፡ ብቻ
፳፬ ውን ፡ በዚያ ፡ ነበረ ። ታንኳይቱም ፡ አሁን ፡ በባ
ሕር ፡ መካከል ፡ ሳለች ፤ ነፋስ ፡ ከወደ ፡ ፊት ፡ ነበ
፳፭ ርና ፡ በማዕበል ፡ ትጨነቅ ፡ ነበር ። ከሌሊቱም ፡
በአራተኛው ፡ ክፍል ፡ ኢየሱስ ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡
፳፮ እየሄደ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ መጣ ። ደቀ ፡ መዛሙ
ርቱም ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡ ሲሄድ ፡ ባዩት ፡ ጊዜ ፡—
ምትሐት ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ታወኩ ፡ በፍርሃትም ፡
፳፯ ጮኹ ። ወዲያውም ፡ ኢየሱስ ፡ ተናገራቸውና ፡—
አይዞአችሁ ፤ እኔ ፡ ነኝ ፤ አትፍሩ ፡ አላቸው ።
፳፰ ጴጥሮስም ፡ መልሶ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፤ አንተስ ፡
ከሆንህ ፡ በውኃው ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እንድ
፳፱ መጣ ፡ እዘዘኝ ፡ አለው ። እርሱም ፡— ና ፡ አለው ።
ጴጥሮስም ፡ ከታንኳይቱ ፡ ወርዶ ፡ ወደ ፡ ኢየ
፴ ሱስ ፡ ሊደርስ ፡ በውኃው ፡ ላይ ፡ ሄደ ። ነገር ፡ ግን ፡
የነፋሱን ፡ ኃይል ፡ አይቶ ፡ ፈራ ፤ ሊሰጥምም ፡
በጀመረ ፡ ጊዜ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፤ አድነኝ ፡ ብሎ ፡
፴፩ ጮኸ ። ወዲያውም ፡ ኢየሱስ ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡
ያዘውና ፡— አንተ ፡ እምነት ፡ የጐደለህ ፤ ስለ ፡
፴፪ ምን ፡ ተጠራጠርህ ? አለው ። ወደ ፡ ታንኳይ
፴፫ ቱም ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፡ ነፋሱ ፡ ተወ ። በታንኳይ
ቱም ፡ የነበሩት ፡— በእውነት ፡ የእግዚአብሔር ፡
ልጅ ፡ ነህ ፡ ብለው ፡ ሰገዱለት ።

፴፬ ተሻግረውም ፡ ወደ ፡ ጌንሴሬጥ ፡ ምድር ፡ መጡ ።
፴፭ የዚያ ፡ ቦታ ፡ ሰዎችም ፡ ባወቁት ፡ ጊዜ ፡ በዙር
ያው ፡ ወዳለ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ላኩ ፤ ሕመምተኞ
፴፮ ችንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አመጡ ፤ የልብሱ
ንም ፡ ጫፍ ፡ ብቻ ፡ ሊዳስሱ ፡ ይለምኑት ፡ ነበር ፤
የዳሰሱትም ፡ ሁሉ ፡ ዳኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያን ፡ ከኢየ
፪ ሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡ ቀረቡና ፡— ደቀ ፡ መዛ
ሙርትህ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ የሽማግሎችን ፡ ወግ ፡
ይተላለፋሉ ? እንጀራ ፡ ሲበሉ ፡ እጃቸውን ፡
፫ አይታጠቡምና ፡ አሉት ። እርሱም ፡ መልሶ ፡ እን
ዲህ ፡ አላቸው ፡— እናንተስ ፡ ስለ ፡ ወጋችሁ ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትተላለፋላ
፬ ችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡— አባትህንና ፡ እናትህን ፡
አክብር ፤ ደግሞ ፡— አባቱን ፡ ወይም ፡ እናቱን ፡
፭ የሰደበ ፡ ፈጽሞ ፡ ይሙት ፡ ብሎአልና ፤ እናንተ ፡
ግን ፡— አባቱን ፡ ወይም ፡ እናቱን ፡— ከእኔ ፡ የምት
፮ ጠቀምበት ፡ መባ ፡ ነው ፡ የሚል ፡ ሁሉ ፤ አባቱን ፡
ወይም ፡ እናቱን ፡ አያከብርም ፡ ትላላችሁ ፤ ስለ ፡
ወጋችሁም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ሽራችሁ ።
፯ እናንተ ፡ ግብዞች ፤ ኢሳይያስ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡—

፰ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ በከንፈሩ ፡ ያከብረኛል ፤ ልቡ ፡
፱ ግን ፡ ከእኔ ፡ በጣም ፡ የራቀ ፡ ነው ፤ የሰውም ፡
ሥርዓት ፡ የሆነ ፡ ትምህርት ፡ እያስተማሩ ፡
በከንቱ ፡ ያመልኩኛል ፡

ብሎ ፡ በእውነት ፡ ትንቢት ፡ ተናገረ ።

፲ ሕዝቡንም ፡ ጠርቶ ፡— ስሙ ፡ አስተውሉም ፤
፲፩ ሰውን ፡ የሚያረክሰው ፡ ወደ ፡ አፍ ፡ የሚገባ ፡
አይደለም ፤ ከአፍ ፡ የሚወጣው ፡ ግን ፡ ሰውን ፡
፲፪ የሚያረክሰው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አላቸው ። በዚያን ፡
ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ቀርበው ፡— ፈሪሳው
ያን ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ሰምተው ፡ እንደ ፡ ተሰናከሉ ፡
፲፫ ለወቅህን ? አሉት ። እርሱ ፡ ግን ፡ መልሶ ፡— የሰ
ማዩ ፡ አባቴ ፡ ያልተከለው ፡ ተክል ፡ ሁሉ ፡ ይነ
፲፬ ቀላል ። ተዉአቸው ፤ ዕውሮችን ፡ የሚመሩ ፡
ዕውሮች ፡ ናቸው ፤ ዕውርም ፡ ዕውርን ፡ ቢመ
ራው ፡ ሁለቱም ፡ ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ ይወድቃሉ ፡

፲፬ ። ፲፫—፳፩ ፡ ማር ፡ ፮ ፡ ፴፪—፵፬ ፡ ሉቃ ፡ ፱ ፡ ፲—፲፯ ፡ ዮሐ ፡ ፮ ፡ ፩—፲፫ ። ፲፱ ፡ ም ፡ ፲ ፡ ፴፮ ። ፲፮—፳ ፡ [illegible] ። ፳፪—፴፫ ፡ ማር ፡ ፮ ፡ ፵፭—፶፪ ፡ ዮሐ ፡ ፮ ፡ ፲፭—፳፩ ። ፴፫ ፡ ማር ፡ ፩ ፡ ፩ ፡ ሉቃ ፡ ፩ ፡ ፴፭ ። ፴፬ ፡ ሉቃ ፡ ፭ ፡ ፩ ። ፴፫ ፡ ም ፡ ፰ ፡ ፳፮ ። ፴፬—፴፮ ፡ ማር ፡ ፮ ፡ ፶፫—፶፮ ። ፴፮ ፡ ም ፡ ፱ ፡ ፳ ።

፲፭ ። ፩—፳ ፡ ማር ፡ ፯ ፡ ፩—፳፫ ። ፪ ፡ ሉቃ ፡ ፲፩ ፡ ፴፰ ። ፬ ፡ ዘፀ ፡ ፳ ፡ ፲፪ ፤ ፳፩ ፡ ፲፯ ። ፰ ፡ ፱ ፡ ኢሳ ፡ ፳፱ ፡ ፲፫ ። ፲፬ ፡ ም ፡ ፳፫ ፡ ፲፮ ፡ ሉቃ ፡ ፮ ፡ ፴፱ ።

፲፭ አለ ። ጴጥሮስም ፡ መልሶ ፡— ምሳሌውን ፡ ተርጕ
፲፮ ምልን ፡ አለው ። ኢየሱስም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—
እናንተ ፡ ደግሞ ፡ እስከሁን ፡ የማታስተውሉ ፡
፲፯ ናችሁን ? ወደ ፡ አፍ ፡ የሚገባ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡
ሆድ ፡ እልፍ ፡ ወደ ፡ እዳሪ ፡ እንዲጣል ፡ አትመ
፲፰ ለከቱምን ? ከአፍ ፡ የሚወጣ ፡ ግን ፡ ከልብ ፡
ይወጣል ፤ ሰውንም ፡ የሚያረክሰው ፡ ያ ፡ ነው ።
፲፱ ከልብ ፡ ክፉ ፡ አሳብ ፤ መግደል ፤ ምንዝርነት ፤
ዝሙት ፤ መስረቅ ፤ በውሸት ፡ መመስከር ፤ ስድብ ፡
፳ ይወጣልና ። ሰውን ፡ የሚያረክሰው ፡ ይህ ፡ ነው ፡
እንጂ ፤ ባልታጠበ ፡ እጅ ፡ መብላትስ ፡ ሰውን ፡
አያረክሰውም ።

፳፩ ኢየሱስም ፡ ከዚያ ፡ ወጥቶ ፡ ወደ ፡ ጢሮስና ፡
፳፪ ወደ ፡ ሲዶና ፡ አገር ፡ ሄደ ። እነሆም ፤ ከነናዊት ፡
ሴት ፡ ከዚያ ፡ አገር ፡ ወጥታ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፤ የዳ
ዊት ፡ ልጅ ፤ ማረኝ ፤ ልጄን ፡ ጋኔን ፡ ክፉኛ ፡ ይዞ
፳፫ አታል ፡ ብላ ፡ ጮኸች ። እርሱ ፡ ግን ፡ አንዳች ፡
አልመለሰላትም ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ቀር
በው ፡— በኋላችን ፡ ትጮኻለችና ፡ አሰናብታት ፡
፳፬ እያሉ ፡ ለመኑት ። እርሱም ፡ መልሶ ፡— ከእስራ
ኤል ፡ ቤት ፡ ለጠፉት ፡ በጎች ፡ በቀር ፡ አልተላክ
፳፭ ሁም ፡ አለ ። እርስዋ ፡ ግን ፡ መጥታ ፡— ጌታ ፡
፳፮ ሆይ ፤ እርዳኝ ፡ እያለች ፡ ሰገደችለት ። እርሱ ፡
ግን ፡ መልሶ ፡— የልጆችን ፡ እንጀራ ፡ ይዞ ፡ ለቡ
፳፯ ችሎች ፡ መጣል ፡ አይገባም ፡ አለ ። እርስዋም ፡—
አዎን ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፤ ቡችሎችም ፡ እኮ ፡ ከጌቶቻ
ቸው ፡ ማዕድ ፡ የወደቀውን ፡ ፍርፋሪ ፡ ይበላሉ ፡
፳፰ አለች ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ኢየሱስ ፡ መልሶ ፡—
አንቺ ፡ ሴት ፤ እምነትሽ ፡ ታላቅ ፡ ነው ፤ እንደ ፡
ወደድሽ ፡ ይሁንልሽ ፡ አላት ። ልጅዋም ፡ ከዚ
ያች ፡ ሰዓት ፡ ጀምሮ ፡ ዳነች ።

፳፱ ኢየሱስም ፡ ከዚያ ፡ አልፎ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡
ባሕር ፡ አጠገብ ፡ መጣ ፤ ወደ ፡ ተራራም ፡ ወጥቶ ፡
፴ በዚያ ፡ ተቀመጠ ። ብዙ ፡ ሕዝብም ፡ አንካሶ
ችን ፤ ዕውሮችንም ፤ ዲዳዎችንም ፤ ጉንድሾች
ንም ፤ ሌሎችንም ፡ ብዙ ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡
ቀረቡ ፤ በኢየሱስም ፡ እግር ፡ አጠገብ ፡ ጣሉአ
፴፩ ቸው ፤ ፈወሳቸውም ፤ ስለዚህም ፡ ሕዝቡ ፡ ዲዳ
ዎች ፡ ሲናገሩ ፤ ጉንድሾችም ፡ ሲድኑ ፤ አንካሶ
ችም ፡ ሲሄዱ ፤ ዕውሮችም ፡ ሲያዩ ፡ አይተው ፡
ተደነቁ ፤ የእስራኤልንም ፡ አምላክ ፡ አከበሩ ።

፴፪ ኢየሱስም ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ ጠርቶ ፡—
ሕዝቡ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ እስከሁን ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡
ውለዋልና ፡ የሚበሉት ፡ ስለ ፡ ሌላቸው ፡ አዝ
ንላቸዋለሁ ፤ በመንገድም ፡ እንዳይዝሉ ፡ ጦማ
ቸውን ፡ ላሰናብታቸው ፡ አልወድም ፡ አላቸው ።
፴፫ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡— ይህን ፡ ያህል ፡ ሕዝብ ፡
የሚያጠግብ ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ እንጀራ ፡ በምድረ ፡
፴፬ በዳ ፡ ከወዴት ፡ እናገኛለን ? አሉት ። ኢየሱ
ስም ፡— ስንት ፡ እንጀራ ፡ አላችሁ ? አላቸው ።
እነርሱም ፡— ሰባት ፤ ጥቂትም ፡ ትንሽ ፡ ዓሣ ፡
፴፭ አሉት ። ሕዝቡም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እንዲቀ
፴፮ መጡ ፡ አዘዘ ፤ ሰባቱንም ፡ እንጀራ ፡ ዓሣውንም ፡
ይዞ ፡ አመስግኖ ፡ ቈረሰ ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡
፴፯ ሰጠ ፤ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ለሕዝቡ ። ሁሉም ፡
በሉና ፡ ጠገቡ ፤ የተረፈውንም ፡ ቍርስራሽ ፡
፴፰ ሰባት ፡ ቅርጫት ፡ ሙሉ ፡ አነሡ ። የበሉትም ፡
ከሴቶችና ፡ ከልጆች ፡ በቀር ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ወን
፴፱ ዶች ፡ ነበሩ ። ሕዝቡንም ፡ ካሰናበተ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡
ታንኳይቱ ፡ ገብቶ ፡ ወደ ፡ መጌዶል ፡ አገር ፡ መጣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ ፈሪሳውያንና ፡ ሰዱቃውያንም ፡ ቀርበው ፡
ሲፈትኑት ፡ ከሰማይ ፡ ምልክት ፡ እንዲያሳያቸው ፡
፪ ለመኑት ። እርሱ ፡ ግን ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አላ
ቸው ፡— በመሸ ፡ ጊዜ ፡— ሰማዩ ፡ ቀልቶአልና ፡
፫ ብራ ፡ ይሆናል ፡ ትላላችሁ ፤ ማለዳም ፡— ሰማዩ ፡
ደምኖ ፡ ቀልቶአልና ፡ ዛሬ ፡ ይዘንባል ፡ ትላላ
ችሁ ። የሰማዩን ፡ ፊት ፡ መለየት ፡ ታውቃላ
ችሁ ፤ የዘመኑንስ ፡ ምልክት ፡ መለየት ፡ አትች
፬ ሉምን ? ክፉና ፡ አመንዝራ ፡ ትውልድ ፡ ምልክት ፡
ይሻል ፤ ከነቢዩም ፡ ከዮናስ ፡ ምልክት ፡ በቀር ፡
ምልክት ፡ አይሰጠውም ። ትቶአቸውም ፡ ሄደ ።
፭ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ወደ ፡ ማዶ ፡ በመጡ ፡
፮ ጊዜ ፡ እንጀራ ፡ መያዝን ፡ ረሱ ። ኢየሱስም ፡—
ከፈሪሳውያንና ፡ ከሰዱቃውያን ፡ እርሾ ፡ ተጠን
፯ ቀቁና ፡ ተጠበቁ ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡— እን
ጀራ ፡ ባንይዝ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡
፰ ተነጋገሩ ። ኢየሱስም ፡ አውቆ ፡ እንዲህ ፡ አላ
ቸው ፡— እናንተ ፡ እምነት ፡ የጐደላችሁ ፤ እን
ጀራ ፡ ስለ ፡ ሌላችሁ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡
፱ ትነጋገራላችሁ ? ገና ፡ አታስተውሉምን ? ለአ
ምስቱ ፡ ሺህ ፡ አምስቱ ፡ እንጀራ ፤ ስንት ፡ መሶ
ብም ፡ እንዳነሣችሁ ፡ ትዝ ፡ አይላችሁምን ?
፲ ወይስ ፡ ለአራቱ ፡ ሺህ ፡ ሰባቱ ፡ እንጀራ ፤ ስንት ፡
ቅርጫትም ፡ እንዳነሣችሁ ፡ ትዝ ፡ አይላችሁ
፲፩ ምን ? ከፈሪሳውያንና ፡ ከሰዱቃውያን ፡ እርሾ ፡
እንድትጠበቁ ፡ ብዬ ፡ ስለ ፡ እንጀራ ፡ እንዳልተ
፲፪ ናገርኋችሁ ፡ እንዴት ፡ አታስተውሉምን ? እነር
ሱም ፡ ከፈሪሳውያንና ፡ ከሰዱቃውያን ፡ ትምህ
ርት ፡ እንጂ ፡ ከእንጀራ ፡ እርሾ ፡ እንዲጠበቁ ፡
እንዳላላቸው ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ አስተዋሉ ።
፲፫ ኢየሱስም ፡ ወደ ፡ ፊልጶስ ፡ ቂሣርያ ፡ አገር ፡
በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡— ሰዎች ፡
የሰውን ፡ ልጅ ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይሉታል ?
፲፬ ብሎ ፡ ጠየቀ ። እነርሱም ፡— አንዳንዱ ፡ መጥ
ምቁ ፡ ዮሐንስ ፤ ሌሎችም ፡ ኤልያስ ፤ ሌሎችም ፡
ኤርምያስ ፡ ወይም ፡ ከነቢያት ፡ አንዱ ፡ ነው ፡

፲፭ ። ፳፩—፳፰ ፡ ማር ፯ ፡ ፳፬—፴ ። ፳፬ ፡ ማቴ ፲ ፡ ፭ ፡ ፮ ። ፳፮ ፡ ማቴ ፯ ፡ ፮ ። ፴፪—፴፱ ፡ ማር ፰ ፡ ፩—፲ ።
፴፪—፴፱ ፡ ማቴ ፲፬ ፡ ፲፬—፳፩ ፡ ማር ፰ ፡ ፩—፲ ።

፲፮ ። ፩—፲፪ ፡ ማቴ ፲፪ ፡ ፴፰ ፡ ማር ፰ ፡ ፲፩—፳፩ ። ፪ ፡ ፫ ፡ ሉቃ ፲፪ ፡ ፶፬—፶፮ ። ፬ ፡ ማቴ ፲፪ ፡ ፴፱ ። ፮ ፡ ሉቃ ፲፪ ፡ ፩ ።
፱ ፡ ማቴ ፲፬ ፡ ፲፯—፳፩ ። ፲ ፡ ማቴ ፲፭ ፡ ፴፬—፴፰ ። ፲፫—፲፮ ፡ ማር ፰ ፡ ፳፯—፳፱ ፡ ሉቃ ፱ ፡ ፲፰—፳ ። ፲፬ ፡ ማቴ ፲፬ ፡ ፪ ፡
ማር ፮ ፡ ፲፬ ፡ ፲፭ ፡ ሉቃ ፱ ፡ ፯ ፡ ፰ ።

፲፭ ይላሉ ፡ አሉት ። እርሱም ፡— እናንተስ ፡ እኔን ፡ ፲፮ ማን ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ትላላችሁ ? አላቸው ። ስምዖን ፡ ጴጥሮስም ፡ መልሶ ፡— አንተ ፡ ክርስቶስ ፡ የሕያው ፡ እግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነህ ፡ አለ ። ፲፯ ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— የዮና ፡ ልጅ ፡ ስምዖን ፡ ሆይ ፥ በሰማያት ፡ ያለው ፡ አባቴ ፡ እንጂ ፡ ሥጋና ፡ ደም ፡ ይህን ፡ አልገለጡልህምና ፡ ብፁዕ ፡ ነህ ። ፲፰ እኔም ፡ እልሃለሁ ፥ አንተ ፡ ጴጥሮስ ፡ ነህ ፥ በዚችም ፡ ዓለት ፡ ላይ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያኔን ፡ እሠራለሁ ፥ የገሃነም ፡ ደጆችም ፡ አይ ፲፱ ችሉአትም ። የመንግሥተ ፡ ሰማያትንም ፡ መክፈቻዎች ፡ እሰጥሃለሁ ፤ በምድር ፡ የምታስረው ፡ ሁሉ ፡ በሰማያት ፡ የታሰረ ፡ ይሆናል ፥ በምድርም ፡ የምትፈታው ፡ ሁሉ ፡ በሰማያት ፡ የተ ፳ ፈታ ፡ ይሆናል ። ያን ፡ ጊዜም ፡ እርሱ ፡ ክርስቶስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለማንም ፡ እንዳይነግሩ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ አዘዛቸው ።

፳፩ ከዚያን ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ ኢየሱስ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ ከሽማግሌዎችና ፡ ከካህናት ፡ አለቆች ፡ ከጻፎችም ፡ ብዙ ፡ መከራ ፡ ይቀበልና ፡ ይገደል ፡ ዘንድ ፡ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ይነሣ ፡ ዘንድ ፡ እንዲገባው ፡ ለደቀ ፡ መዛሙ ፳፪ ርቱ ፡ ይገልጥላቸው ፡ ጀመር ። ጴጥሮስም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ወስዶ ፡— አይሁንብህ ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፤ ይህ ፡ ከቶ ፡ አይደርስብህም ፡ ብሎ ፡ ሊገሥጸው ፡ ፳፫ ጀመረ ። እርሱ ፡ ግን ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ጴጥሮስን ፡— ወደ ፡ ኋላዬ ፡ ሂድ ፥ አንተ ፡ ሰይጣን ፤ የሰው ፡ እንጂ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ አታስብምና ፡ ዕንቅፋት ፡ ሆነህብኛል ፡ አለው ።

፳፬ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ኢየሱስ ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— እኔን ፡ መከተል ፡ የሚወድ ፡ ቢኖር ፥ ራሱን ፡ ይካድ ፡ መስቀሉንም ፡ ተሸክሞ ፡ ፳፭ ይከተለኝ ። ነፍሱን ፡ ሊያድን ፡ የሚወድ ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋታል ፤ ስለ ፡ እኔ ፡ ግን ፡ ነፍሱን ፡ የሚያ ፳፮ ጠፋ ፡ ሁሉ ፡ ያገኛታል ። ሰው ፡ ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ ቢያተርፍ ፡ ነፍሱንም ፡ ቢያጐድል ፡ ምን ፡ ይጠቀማል ? ወይስ ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ ነፍሱ ፡ ቤዛ ፡ ፳፯ ምን ፡ ይሰጣል ? የሰው ፡ ልጅ ፡ ከመላእክቱ ፡ ጋር ፡ በአባቱ ፡ ክብር ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ አለውና ፤ ያን ፡ ጊዜም ፡ ለሁሉ ፡ እንደ ፡ ሥራው ፡ ያስረክ ፳፰ በዋል ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ በመንግሥቱ ፡ ሲመጣ ፡ እስኪያዩ ፡ ድረስ ፡ እዚህ ፡ ከሚቆሙት ፡ ሞትን ፡ የማይቀምሱ ፡ አንዳንድ ፡ አሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ ከስድስት ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ኢየሱስ ፡ ጴጥሮስንና ፡ ያዕቆብን ፡ ወንድሙንም ፡ ዮሐንስን ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ረጅም ፡ ተራራ ፡ ብቻቸውን ፡ አወጣ ፪ ቸው ። በፊታቸውም ፡ ተለወጠ ፥ ፊቱም ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡ በራ ፥ ልብሱም ፡ እንደ ፡ ብርሃን ፡ ነጭ ፡ ፫ ሆነ ። እነሆም ፥ ሙሴና ፡ ኤልያስ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ፬ ሲነጋገሩ ፡ ታዩአቸው ። ጴጥሮስም ፡ መልሶ ፡ ኢየሱስን ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ በዚህ ፡ መሆን ፡ ለእኛ ፡ መልካም ፡ ነው ፤ ብትወድስ ፥ በዚህ ፡ ሦስት ፡ዳስ ፡ አንዱን ፡ ለአንተ ፡ አንዱንም ፡ ለሙሴ ፡ ፭ አንዱንም ፡ ለኤልያስ ፡ እንሥራ ፡ አለ ። እርሱም ፡ ገና ፡ ሲናገር ፥ እነሆ ፥ ብሩህ ፡ ደመና ፡ ጋረዳ ቸው ፥ እነሆም ፥ ከደመናው ፡— በእርሱ ፡ ደስ ፡ የሚለኝ ፡ የምወደው ፡ ልጄ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ እርሱን ፡ ፮ ስሙት ፡ የሚል ፡ ድምፅ ፡ መጣ ። ደቀ ፡ መዛሙ ርቱም ፡ ሰምተው ፡ በፊታቸው ፡ ወደቁ ፡ እጅ ፯ ግም ፡ ፈርተው ፡ ነበር ። ኢየሱስም ፡ ቀርቦ ፡ ዳሰሳቸውና ፡— ተነሡ ፡ አትፍሩም ፡ አላቸው ። ፰ ዓይናቸውንም ፡ አቅንተው ፡ ሲያዩ ፡ ከኢየሱስ ፡ ብቻ ፡ በቀር ፡ ማንንም ፡ አላዩም ።

፱ ከተራራውም ፡ በወረዱ ፡ ጊዜ ፡ ኢየሱስ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ከሙታን ፡ እስኪነሣ ፡ ድረስ ፡ ያያችሁትን ፡ ለማንም ፡ አትንገሩ ፡ ብሎ ፡ አዘ ፲ ዛቸው ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡— እንግዲህ ፡ ጻፎች ፡— ኤልያስ ፡ አስቀድሞ ፡ ሊመጣ ፡ ይገባ ዋል ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይላሉ ? ብለው ፡ ጠየቁት ። ፲፩ ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡— ኤልያስማ ፡ አስቀድሞ ፡ ፲፪ ይመጣል ፡ ሁሉንም ፡ ያቀናል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እላች ኋለሁ ፥ ኤልያስ ፡ ከዚህ ፡ በፊት ፡ መጣ ፤ የወደ ዱትንም ፡ ሁሉ ፡ አደረጉበት ፡ እንጂ ፡ አላወቁ ትም ፤ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ከእ ነርሱ ፡ መከራ ፡ ይቀበል ፡ ዘንድ ፡ አለው ፡ አላ ፲፫ ቸው ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ስለ ፡ መጥምቁ ፡ ስለ ፡ ዮሐንስ ፡ እንደ ፡ ነገራቸው ፡ አስተዋሉ ።

፲፬ ወደ ፡ ሕዝቡም ፡ ሲደርሱ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ፲፭ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀረበና ፡ ተንበርክኮ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ልጄን ፡ ማርልኝ ፥ በጨረቃ ፡ እየተነሣበት ፡ ክፉኛ ፡ ይሣቀያልና ፤ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ በእሳት ፡ ብዙ ፡ ፲፮ ጊዜም ፡ በውኃ ፡ ይወድቃልና ። ወደ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርትህም ፡ አመጣሁት ፡ ሊፈውሱትም ፡ ፲፯ አቃታቸው ፡ አለው ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡— የማታምን ፡ ጠማማ ፡ ትውልድ ፡ ሆይ ፥ እስከ ፡ መቼ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እኖራለሁ ? እስከ ፡ መቼስ ፡ እታገሣችኋለሁ ? ወደዚህ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ፲፰ አምጡት ፡ አለ ። ኢየሱስም ፡ ገሠጸው ፡ ጋኔ ኑም ፡ ከእርሱ ፡ ወጣ ፥ ብላቴናውም ፡ ከዚያች ፡ ፲፱ ሰዓት ፡ ጀምሮ ፡ ተፈወሰ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ብቻቸውን ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡ ቀረ ቡና ፡— እኛ ፡ ልናወጣው ፡ ያልቻልን ፡ ስለ ፡

፲፮ ። ፲፬ ፤ ምዕ. ፲፬ ፥ ፪ ፤ ዮሐ. ፩ ፥ ፳፩ ። ፲፮ ፡ ፲፯ ፤ ዮሐ. ፮ ፥ ፷፱ ። ፲፱ ፤ ምዕ. ፲፰ ፥ ፲፰ ፤ ዮሐ. ፳ ፥ ፳፫ ። ፳ ፤ ምዕ. ፲፯ ፥ ፱ ፤ ማር. ፰ ፥ ፴ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፳፩ ። ፳፩ — ፳፰ ፤ ማር. ፰ ፥ ፴፩ — ፱ ፥ ፩ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፳፪ — ፳፯ ። ፳፩ ፤ ምዕ. ፲፯ ፥ ፳፪ ፡ ፳፫ ፤ ፳ ፥ ፲፰ ፡ ፲፱ ፤ ማር. ፰ ፥ ፴፩ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፳፪ ፤ ዮሐ. ፲፪ ፥ ፴፫ ፡ ፴፬ ። ፳፬ ፡ ፳፭ ፤ ምዕ. ፲ ፥ ፴፰ ፡ ፴፱ ። ፳፯ ፤ ምዕ. ፳ ፥ ፴፩ ፤ ፳፭ ፥ ፴፩ ፤ ፳፯ ፥ ፳፱ ።

፲፯ ። ፩ — ፰ ፤ ማር. ፱ ፥ ፪ — ፰ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፳፰ — ፴፮ ። ፭ ፤ ምዕ. ፫ ፥ ፲፯ ። ፰ ፤ ምዕ. ፫ ፥ ፲፫ ፡ ፲፮ ፤ ፪ ጴጥ. ፩ ፥ ፲፯ ። ፱ — ፲፫ ፤ ማር. ፱ ፥ ፱ — ፲፫ ። ፲ ፤ ምዕ. ፲፩ ፥ ፲፬ ። ፲፫ ፤ ሉቃ. ፩ ፥ ፲፯ ። ፲፬ ፤ ምዕ. ፲፬ ፥ ፲ — ፲፱ ። ፲፬ — ፲፰ ፤ ማር. ፱ ፥ ፲፬ — ፳፯ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፴፯ — ፵፪ ።

፳ ምን ፡ ነው ? አሉት ። ኢየሱስም ፡— ስለ ፡ እምነ ታችሁ ፡ ማነስ ፡ ነው ፤ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ የሰ ናፍጭ ፡ ቅንጣት ፡ የሚያህል ፡ እምነት ፡ ቢኖራ ችሁ ፥ ይህን ፡ ተራራ ፡— ከዚህ ፡ ወደዚያ ፡ እለፍ ፡ ብትሉት ፡ ያልፋል ፤ የሚሳናችሁም ፡ ነገር ፡
፳፩ የለም ። ይህ ፡ ዓይነት ፡ ግን ፡ ከጸሎትና ፡ ከጦም ፡ በቀር ፡ አይወጣም ፡ አላቸው ።

፳፪ በገሊላም ፡ ሲመላለሱ ፡ ኢየሱስ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ በሰዎች ፡ እጅ ፡ አልፎ ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡
፳፫ አለው ፤ ይገድሉትማል ፥ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ይነሣል ፡ አላቸው ። እጅግም ፡ አዘኑ ።

፳፬ ወደ ፡ ቅፍርናሆምም ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ግብር ፡ የሚቀበሉ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ጴጥሮስ ፡ ቀረቡና ፡— መምህራችሁ ፡ ሁለቱን ፡ ዲናር ፡(1) አይገብር
፳፭ ምን ? አሉት ። እምን ፡ ይገብራል ፡ አለ ። ወደ ፡ ቤትም ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ኢየሱስ ፡ አስቀድሞ ፡— ስምዖን ፡ ሆይ ፥ ምን ፡ ይመስልሃል ? የምድር ፡ ነገሥታት ፡ ቀረጥና ፡ ግብር ፡ ከማን ፡ ይቀበላሉ ? ከልጆቻቸውን ፡ ወይስ ፡ ከእንግዶች ? አለው ።
፳፮ ጴጥሮስም ፡— ከእንግዶች ፡ በለው ፡ ጊዜ ፡ ኢየ ሱስ ፡— እንኪያስ ፡ ልጆቻቸው ፡ ነጻ ፡ ናቸው ።
፳፯ ነገር ፡ ግን ፡ እንዳናሰናክላቸው ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ሂድና ፡ መቃጥን ፡ ጣል ፥ መጀመሪያም ፡ የሚ ወጣውን ፡ ዓሣ ፡ ውሰድና ፡ አፉን ፡ ስትከፍት ፡ እስታቴር ፡(2) ታገኛለህ ፤ ያን ፡ወስደህ ፡ ስለ ፡ እኔና ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ ስጣቸው ፡ አለው ።

(1) አንድ ፡ ዲናር ፡ አምሳ ፡ የኢት ፡ ብር ፡ ሳንቲም ፡ ያህል ፡ ነው ።
(2) እስታቴር ፡ ሁለት ፡ ብር ፡ ያህል ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ በዚያች ፡ ሰዓት ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡ ቀርበው ፡— በመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ከሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ ማን ፡ ይሆን ? አሉት ።
፪ ሕፃንም ፡ ጠርቶ ፡ በመካከላቸው ፡ አቆመ ፡
፫ እንዲህም ፡ አለ ፡— እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ካል ተመለሳችሁ ፡ እንደ ፡ ሕፃናትም ፡ ካልሆናችሁ ፥ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ከቶ ፡ አትገቡም ።
፬ እንግዲህ ፡ እንደዚህ ፡ ሕፃን ፡ ራሱን ፡ የሚያዋ ርድ ፡ ሁሉ ፥ በመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ የሚበልጥ ፡ እርሱ ፡ ነው ።
፭ እንደዚህም ፡ ያለውን ፡ አንድ ፡ ሕፃን ፡ በስሜ ፡
፮ የሚቀበል ፡ ሁሉ ፡ እኔን ፡ ይቀበላል ፤ በእኔም ፡ ከሚያምኑ ፡ ከነዚህ ፡ ከታናናሾቹ ፡ እንዱን ፡ የሚያሰናክል ፡ ሁሉ ፥ የወፍጮ ፡ ድንጋይ ፡ በአ ንገቱ ፡ ታስሮ ፡ ወደ ፡ ጥልቅ ፡ ባሕር ፡ መስጠም ፡ ይሻለው ፡ ነበር ።
፯ ወዮ ፡ ለዓለም ፡ ስለ ፡ ማሰናከያ ፤ ማሰናከያ ፡ ሳይ መጣ ፡ አይቀርምና ፥ ነገር ፡ ግን ፡ በእርሱ ፡ ጠንቅ ፡ ማሰናከያ ፡ ለሚመጣበት ፡ ለዚያ ፡ ሰው ፡ ወዮ
፰ ለት ። እጅህ ፡ ወይም ፡ እግርህ ፡ ብታሰናክልህ ፥ ቈርጠህ ፡ ከአንተ ፡ ጣላት ፤ ሁለት ፡ እጅ ፡ ወይም ፡ ሁለት ፡ እግር ፡ ኖሮህ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ እሳት ፡ ከምትጣል ፡ ይልቅ ፡ አንካሳ ፡ ወይም ፡ ጕንድሽ ፡ ሆነህ ፡ ወደ ፡ ሕይወት ፡ መግባት ፡ ይሻልሃል ።
፱ ዓይንህ ፡ ብታሰናክልህ ፡ አውጥተህ ፡ ከአንተ ፡ ጣላት ፤ ሁለት ፡ ዓይን ፡ ኖሮህ ፡ ወደ ፡ ገሃነመ ፡ እሳት ፡ ከምትጣል ፡ ይልቅ ፡ አንዲት ፡ ዓይን ፡ ኖራህ ፡ ወደ ፡ ሕይወት ፡ መግባት ፡ ይሻልሃል ።
፲ ከነዚህ ፡ ከታናናሾቹ ፡ አንዱን ፡ እንዳትንቁ ፡ ተጠንቀቁ ፤ መላእክቶቻቸው ፡ በሰማያት ፡ ዘወ ትር ፡ በሰማያት ፡ ያለውን ፡ የአባቴን ፡ ፊት ፡
፲፩ ያያሉ ፡ እላችኋለሁና ። የሰው ፡ ልጅ ፡ የጠፋ
፲፪ ውን ፡ ለማዳን ፡ መጥቶአልና ። ምን ፡ ይመስላች ኋል ? ለአንድ ፡ ሰው ፡ መቶ ፡ በጎች ፡ ቢኖሩት ፡ ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ ቢበዝን ፥ ዘጠና ፡ ዘጠኙን ፡ በተራራ ፡ ትቶ ፡ ሄዶም ፡ የበዘነውን ፡ አይፈልግ
፲፫ ምን ? ቢያገኘውም ፥ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ካልበዘኑት ፡ ከዘጠና ፡ ዘጠኙ ፡ ይልቅ ፡ በእርሱ ፡
፲፬ ደስ ፡ ይለዋል ። እንደዚሁ ፡ ከእነዚህ ፡ ከታና ናሾቹ ፡ አንዱ ፡ እንዲጠፋ ፡ በሰማያት ፡ ያለው ፡ አባታችሁ ፡ ፈቃድ ፡ አይደለም ።
፲፭ ወንድምህም ፡ ቢበድልህ ፥ ሄደህ ፡ አንተና ፡ እርሱ ፡ ብቻችሁን ፡ ሆናችሁ ፡ ውቀሰው ። ቢሰ
፲፮ ማህ ፥ ወንድምህንግን ፡ ዳግም ፡ አደረግኸው ፤ ባይሰማ ህ ፡ ግን ፥ በሁለት ፡ ወይም ፡ በሦስት ፡ ምስክር ፡ አፍ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እንዲጸና ፥ ዳግመኛ ፡ አንድ ፡
፲፯ ወይም ፡ ሁለት ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ውሰድ ፤ እነር ሱንም ፡ ባይሰማ ፥ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ንገራት ፤ ደግሞም ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ባይሰማት ፥ እንደ ፡
፲፰ አረመኔና ፡ እንደ ፡ ቀራጭ ፡ ይሁንልህ ። እው ነት ፡ እላችኋለሁ ፥ በምድር ፡ የምታስሩት ፡ ሁሉ ፡ በሰማይ ፡ የታሰረ ፡ ይሆናል ፥ በምድርም ፡ የም ትፈቱት ፡ ሁሉ ፡ በሰማይ ፡ የተፈታ ፡ ይሆናል ።
፲፱ ደግሞ ፡ እላችኋለሁ ፥ ከእናንተ ፡ ሁለቱ ፡ በም ድር ፡ በማናቸውም ፡ በሚለምኑት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ቢስማሙ ፡ በሰማያት ፡ ካለው ፡ ከአባቴ ፡ ዘንድ ፡
፳ ይደረግላቸዋል ። ሁለት ፡ ወይም ፡ ሦስት ፡ በስሜ ፡ በሚሰበሰቡበት ፡ በዚያ ፡ በመካከላቸው ፡ እሆና ለሁና ።
፳፩ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ጴጥሮስ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀርቦ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ወንድሜ ፡ ቢበድለኝ ፡ ስንት ፡ ጊዜ ፡ ልተውለት ? እስከ ፡ ሰባት ፡ ጊዜን ? አለው ።
፳፪ ኢየሱስ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— እስከ ፡ ሰባ ፡ ጊዜ ፡ ሰባት ፡ እንጂ ፡ እስከ ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ አልልህም ።
፳፫ ስለዚህ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ባሮቹን ፡ ሊቈጣጠር ፡ የወደደን ፡ ንጉሥ ፡ ትመስላለች ።
፳፬ መቈጣጠርም ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፥ እልፍ ፡ መክ ሊት ፡ ዕዳ ፡ ያለበትን ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡

፲፯ ። [illegible]

፲፰ ። [illegible]

፳፭ አመጡ ። የሚከፍለውም ፡ ቢያጣ ፡ እርሱና ፡ ሚስቱ ፡ ልጆቹም ፡ ያለውም ፡ ሁሉ ፡ እንዲሸ ፳፮ ጥና ፡ ዕዳው ፡ እንዲከፈል ፡ ጌታው ፡ አዘዘ ። ስለ ዚህ ፡ ባሪያው ፡ ወድቆ ፡ ሰገደለትና ፦ ጌታ ፡ ሆይ ÷ ታገሠኝ ÷ ሁሉንም ፡ እከፍልሃለሁ ፡ አለው ። ፳፯ የዚያም ፡ ባሪያ ፡ ጌታ ፡ አዘነለትና ፡ ለቀቀው ÷ ዕዳ ፳፰ ውንም ፡ ተወለት ። ነገር ፡ ግን ፡ ያ ፡ ባሪያ ፡ ወጥቶ ፡ ከባልንጀሮቹ ፡ ከባሮቹ ፡ መቶ ፡ ዲናር ፡ ዕዳ ፡ ያለ በትን ፡ አንዱን ፡ አገኘና ፦ ዕዳህን ፡ ክፈለኝ ፡ ፳፱ ብሎ ፡ ያዘና ፡ አነቀው ። ስለዚህ ፡ ባልንጀራው ፡ ባሪያ ፡ ወድቆ ፦ ታገሠኝ ÷ ሁሉንም ፡ እከፍልሃ ፴ ለሁ ፡ ብሎ ፡ ለመነው ። እርሱም ፡ አልወደደም ÷ ግን ፡ ሄዶ ፡ ዕዳውን ፡ እስኪከፍል ፡ ድረስ ፡ በወ ፴፩ ኅኒ ፡ አኖረው ። ባልንጀሮቹ ፡ የሆኑ ፡ ባሮችም ፡ ያደረገውን ፡ አይተው ፡ እጅግ ፡ አዘኑ ÷ መጥተ ውም ፡ የሆነውን ፡ ሁሉ ፡ ለጌታቸው ፡ ገለጡ ። ፴፪ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ጌታው ፡ ጠርቶ ፦ አንተ ፡ ክፉ ፡ ባሪያ ÷ ስለ ፡ ለመንኸኝ ፡ ያን ፡ ዕዳ ፡ ሁሉ ፡ ተው ፴፫ ሁልህ ፤ እኔ ፡ እንደ ፡ ማርሁህ ፡ ባልንጀራህ ፡ የሆነውን ፡ ያን ፡ ባሪያ ፡ ልትምረው ፡ ለአንተስ ፴፬ አይገባህምን ? አለው ። ጌታውም ፡ ተቈጣና ፡ ዕዳውን ፡ ሁሉ ፡ እስኪከፍለው ፡ ድረስ ፡ ለሚሣ ፴፭ ቀዩት ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠው ። ከእናንተ ፡ እያንዳ ንዱ ፡ ወንድሙን ፡ ከልቡ ፡ ይቅር ፡ ካላለ ÷ እን ዲሁ ፡ ደግሞ ፡ የሰማዩ ፡ አባቴ ፡ ያደርግባችኋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ ኢየሱስም ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ከፈጸመ ፡ በኋላ ÷ ከገሊላ ፡ ሄዶ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ አውራጃ ፡ ወደ ፡ ፪ ዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ መጣ ። ብዙ ፡ ሕዝብም ፡ ተከ ተሉት ÷ በዚያም ፡ ፈወሳቸው ።

፫ ፈሪሳውያንም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀረቡና ፡ ሲፈት ኑት ፦ ሰው ፡ በሆነው ፡ ምክንያት ፡ ሁሉ ፡ ሚስ ቱን ፡ ሊፈታ ፡ ተፈቅዶለታልን ? አሉት ። ፬ እርሱ ፡ ግን ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ ፈጣሪ ፡ በመጀመሪያ ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ አደረጋቸው ÷ ፭ አለም ፦ ስለዚህ ፡ ሰው ፡ አባቱንና ፡ እናቱን ፡ ይተዋል ÷ ከሚስቱም ፡ ጋር ፡ ይተባበራል ÷ ሁለ ቱም ፡ አንድ ፡ ሥጋ ፡ ይሆናሉ ፡ የሚለውን ፡ ፮ ቃል ፡ አላነበባችሁምን ? ስለዚህ ፡ አንድ ፡ ሥጋ ፡ ናቸው ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ሁለት ፡ አይ ደሉም ። እግዚአብሔር ፡ ያጣመረውን ፡ እንግ ፯ ዲህ ፡ ሰው ፡ አይለየው ። እነርሱም ፦ እንኪ ያስ ፡ ሙሴ ፡ የፍችዋን ፡ ጽሕፈት ፡ ሰጥተው ፡ እን ፰ ዲፈቱአት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አዘዘ ? አሉት ። እር ሱም ፦ ሙሴስ ፡ ስለ ፡ ልባችሁ ፡ ጥንከሬ ፡ ሚስ ቶቻችሁን ፡ ትፈቱ ፡ ዘንድ ፡ ፈቀደላችሁ ፤ ከጥ ፱ ንት ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አልነበረም ። እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ÷ ያለ ፡ ዝሙት ፡ ምክንያት ፡ ሚስ ቱን ፡ ፈትቶ ፡ ሌላዪቱን ፡ የሚያገባ ፡ ሁሉ ፡ ያመ ነዝራል ÷ የተፈታችውንም ፡ የሚያገባ ፡ ያመነ ዝራል ፡ አላቸው ።

፲ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፦ የባልና ፡ የሚስት ፡ ሥርዓት ፡ እንዲህ ፡ ከሆነ ፡ መጋባት ፡ አይጠቅ ፲፩ ምም ፡ አሉት ። እርሱ ፡ ግን ፦ ይህ ፡ ነገር ፡ ለተ ፲፪ ሰጣቸው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ለሁሉ ፡ አይደለም ፤ በእ ናት ፡ ማኅፀን ፡ ጃንደረቦች ፡ ሆነው ፡ የተወለዱ ፡ አሉ ÷ ሰውም ፡ የሰለባቸው ፡ ጃንደረቦች ፡ አሉ ÷ ስለ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያትም ፡ ራሳቸውን ፡ የሰ ለቡ ፡ ጃንደረቦች ፡ አሉ ። ሊቀበለው ፡ የሚችል ፡ ይቀበለው ፡ አላቸው ።

፲፫ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እጁን ፡ እንዲጭንባቸውና ፡ እን ዲጸልይ ፡ ሕፃናትን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አመጡ ፤ ደቀ ፡ ፲፬ መዛሙርቱም ፡ ገሠጹአቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ ኢየ ሱስ ፦ ሕፃናትን ፡ ተዉአቸው ÷ ወደ ፡ እኔም ፡ ይመጡ ፡ ዘንድ ፡ አትከልክሉአቸው ፤ መንግ ሥተ ፡ ሰማያት ፡ እንደነዚህ ፡ ላሉ ፡ ናትና ፡ አለ ፤ ፲፭ እጁንም ፡ ጫነባቸውና ፡ ከዚያ ፡ ሄደ ።

፲፮ እነሆም ÷ አንድ ፡ ሰው ፡ ቀርቦ ፦ መምህር ፡ ሆይ ÷ የዘላለምን ፡ ሕይወት ፡ እንዳገኝ ፡ ምን ፡ ፲፯ መልካም ፡ ነገር ፡ ላድርግ ? አለው ። እርሱም ፦ ስለ ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ለምን ፡ ትጠይቀኛለህ ? መልካም ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ ነው ፤ ወደ ፡ ሕይወት ፡ መግባት ፡ ብትወድ ፡ ግን ፡ ትእዛዛትን ፡ ጠብቅ ፡ ፲፰ አለው ። እርሱም ፦ የትኞችን ? አለው ። ኢየ ሱስም ፦ አትግደል ÷ አታመንዝር ÷ አትስ ፲፱ ረቅ ÷ በሐሰት ፡ አትመስክር ÷ አባትህንና ፡ እና ትህን ፡ አክብር ÷ ባልንጀራህንም ፡ እንደ ፡ ራስህ ፡ ፳ ውደድ ፡ አለው ። ጐበዙም ፦ ይህንማ ፡ ሁሉ ፡ ከሕፃንነቴ ፡ጀምሬ ፡ ጠብቄአለሁ ÷ ደግሞስ ፡ ፳፩ የሚጐድለኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለው ። ኢየሱ ስም ፦ ፍጹም ፡ ልትሆን ፡ ብትወድ ÷ ሂድና ፡ ያለህን ፡ ሸጠህ ፡ ለድሆች ፡ ስጥ ÷ መዝገብም ፡ በሰማያት ፡ ታገኛለህ ÷ መጥተህም ፡ ተከተ ፳፪ ለኝ ፡ አለው ። ጐበዙም ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ ንብረት ፡ ነበረውና ፡ እያ ዘነ ፡ ሄደ ።

፳፫ ኢየሱስም ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፦ እውነት ፡ እላችኋለሁ ÷ ለባለጠጋ ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማ ፳፬ ያት ፡ መግባት ፡ ጭንቅ ፡ ነው ። ዳግመኛም ፡ እላ ችኋለሁ ÷ ባለጠጋ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግ ሥት ፡ ከሚገባ ፡ ግመል ፡ በመርፌ ፡ ቀዳዳ ፡ ቢገባ ፡ ፳፭ ይቀላል ፡ አለ ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ሰም ተው ፡ እጅግ ፡ ተገረሙና ፦ እንኪያስ ፡ ማን ፡ ፳፮ ሊድን ፡ ይችላል ? አሉ ። ኢየሱስም ፡ እነርሱን ፡ ተመልክቶ ፦ ይህ ፡ በሰው ፡ ዘንድ ፡ አይቻልም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ግን ፡ ሁሉ ፡ ይቻላል ፡ ፳፯ አላቸው ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ጴጥሮስ ፡ መልሶ ፦ እነሆ ÷ እኛ ፡ ሁሉን ፡ ትተን ፡ ተከተልንህ ፤ እን

፲፰ ። ፳፰ ፡ [illegible]

፲፱ ። ፩—፱ ፡ ማር ፡ ፲ ፡ ፩—፲፪ ። [illegible]

፳፯ ዲያስ ፡ ምን ፡ እናገኝ ፡ ይሆን ? አለው ። ኢየ
ሱስም ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— እውነት ፡ እላች
ኋለሁ ፥ እናንተስ ፡ የተከተላችሁኝ ፥ በዳግመኛ ፡
ልደት ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በክብሩ ፡ ዙፋን ፡ በሚቀ
መጥበት ፡ ጊዜ ፥ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ በአሥራ ፡
ሁለቱ ፡ የእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ስትፈርዱ ፡ በአ
፳፱ ሥራ ፡ ሁለት ፡ ዙፋን ፡ ትቀመጣላችሁ ። ስለ ፡
ስሜም ፡ ቤቶችን ፡ ወይም ፡ ወንድሞችን ፡ ወይም ፡
እኅቶችን ፡ ወይም ፡ አባትን ፡ ወይም ፡ እናትን ፡
ወይም ፡ ሚስትን ፡ ወይም ፡ ልጆችን ፡ ወይም ፡
እርሻን ፡ የተወ ፡ ሁሉ ፡ መቶ ፡ እጥፍ ፡ ይቀበላል ፡
፴ የዘላለምንም ፡ ሕይወት ፡ ይወርሳል ። ነገር ፡
ግን ፡ ብዙዎቹ ፡ ፊተኞች ፡ ኋለኞች ፥ ኋለኞችም ፡
ፊተኞች ፡ ይሆናሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ለወይኑ ፡ አትክልት ፡
ሠራተኞችን ፡ ሊቀጥር ፡ ማልዶ ፡ የወጣ ፡ በለ
፪ ቤት ፡ ሰውን ፡ ትመስላለችና ። ሠራተኞችንም ፡
በቀን ፡ አንድ ፡ ዲናር ፡ ተስማምቶ ፡ ወደ ፡ ወይኑ ፡
፫ አትክልት ፡ ሰደዳቸው ። በሦስት ፡ ሰዓትም ፡
ወጥቶ ፡ ሥራ ፡ የፈቱ ፡ ሌሎችን ፡ በአደባባይ ፡
፬ ቆመው ፡ አየ ፥ እነዚያንም ፡— እናንተ ፡ ደግሞ ፡
ወደ ፡ ወይኔ ፡ አትክልት ፡ ሂዱ ፡ የሚገባውንም ፡
እሰጣችኋለሁ ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡ ሄዱ ።
፭ ደግሞም ፡ በስድስትና ፡ በዘጠኝ ፡ ሰዓት ፡ ወጥቶ ፡
፮ እንዲሁ ፡ አደረገ ። በአሥራ ፡ አንደኛውም ፡
ሰዓት ፡ ወጥቶ ፡ ሌሎችን ፡ ቆመው ፡ አገኘና ፡—
ሥራ ፡ ፈትታችሁ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ በዚህ ፡ ስለ ፡
፯ ምን ፡ ትቆማላችሁ ? አላቸው ። የሚቀጥረን ፡
ስለ ፡ አጣን ፡ ነው ፡ አሉት ። እርሱም ፡— እናንተ ፡
ደግሞ ፡ ወደ ፡ ወይኔ ፡ አትክልት ፡ ሂዱ ፡ የሚገ
፰ ባውንም ፡ ትቀበላላችሁ ፡ አላቸው ። በመሸም ፡
ጊዜ ፡ የወይኑ ፡ አትክልት ፡ ጌታ ፡ አዛዡን ፡— ሠራ
ተኞችን ፡ ጥራና ፡ ከኋለኞች ፡ ጀምረህ ፡ እስከ ፡
ፊተኞች ፡ ድረስ ፡ ደመወዝ ፡ ስጣቸው ፡ አለው ።
፱ በአሥራ ፡ አንደኛው ፡ ሰዓትም ፡ የገቡ ፡ መጥ
ተው ፡ እያንዳንዳቸው ፡ አንድ ፡ ዲናር ፡ ተቀ
፲ በሉ ። ፊተኞችም ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ አብዝተው ፡
የሚቀበሉ ፡ መስሎአቸው ፡ ነበር ፤ እነርሱም ፡
ደግሞ ፡ እያንዳንዳቸው ፡ አንድ ፡ ዲናር ፡ ተቀ
፲፩ ፡ ፲፪ በሉ ። ተቀብለውም ፡— እነዚህ ፡ ኋለኞች ፡ አንድ ፡
ሰዓት ፡ ሠሩ ፥ የቀኑንም ፡ ድካምና ፡ ትኩሳት ፡
ከተሸከምን ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ አስተካከልሃቸው ፡
፲፫ ብለው ፡ በባለቤቱ ፡ ላይ ፡ አንጐራጐሩ ። እርሱ ፡
ግን ፡ መልሶ ፡ ከእነርሱ ፡ ለአንዱ ፡ እንዲህ ፡
አለው ፡— ወዳጄ ፡ ሆይ ፥ አልበደልሁህም ፡ በአ
፲፬ ንድ ፡ ዲናር ፡ አልተስማማህኝምን ? ድርሻህን ፡
ውሰድና ፡ ሂድ ፤ እኔ ፡ ለዚህ ፡ ለኋለኛው ፡ እንደ ፡
አንተ ፡ ልሰጠው ፡ እወዳለሁ ፤ በገንዘቤ ፡ የወደ ፲፭
ድሁትን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ መብት ፡ የለኝምን ?
ወይስ ፡ እኔ ፡ መልካም ፡ ስለ ፡ ሆንሁ ፡ ዓይንህ ፡
ምቀኛ ፡ ናትን ? እንዲሁ ፡ ኋለኞች ፡ ፊተኞች ፥ ፲፮
ፊተኞችም ፡ ኋለኞች ፡ ይሆናሉ ፤ የተጠሩ ፡
ብዙዎች ፥ የተመረጡ ፡ ግን ፡ ጥቂቶች ፡ ናቸውና ።

ኢየሱስም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሊወጣ ፡ ፲፯
ሳለ ፥ በመንገድ ፡ አሥራ ፡ ሁለቱን ፡ ደቀ ፡ መዛ
ሙርት ፡ ብቻቸውን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አቅርቦ ፡—
እነሆ ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እንወጣለን ፥ የሰው ፡ ፲፰
ልጅም ፡ ለካህናት ፡ አለቆችና ፡ ለጻፎች ፡ ይሰ
ጣል ፤ የሞት ፡ ፍርድም ፡ ይፈርዱበታል ፥
ሊዘባበቱበትም ፡ ሊገርፉትም ፡ ሊሰቅሉትም ፡ ፲፱
ለአሕዛብ ፡ አሳልፈው ፡ ይሰጡታል ፥ በሦስተኛ
ውም ፡ ቀን ፡ ይነሣል ፡ አላቸው ።

በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የዘብዴዎስ ፡ ልጆች ፡ እናት ፡ ፳
ከልጆችዋ ፡ ጋር ፡ እየሰገደችና ፡ አንድ ፡ ነገር ፡
እየለመነች ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀረበች ። እርሱም ፡— ፳፩
ምን ፡ ትፈልጊያለሽ ? አላት ። እርስዋም ፡— እነ
ዚህ ፡ ሁለቱ ፡ ልጆቼ ፡ አንዱ ፡ በቀኝህ ፡ አንዱም ፡
በግራህ ፡ በመንግሥትህ ፡ እንዲቀመጡ ፡ እዘዝ ፡
አለችው ። ኢየሱስ ፡ ግን ፡ መልሶ ፡— የምትለም ፳፪
ኑትን ፡ አታውቁም ። እኔ ፡ ልጠጣው ፡ ያለውን ፡
ጽዋ ፡ ልትጠጡ ፡ እኔም ፡ የምጠመቀውን ፡ ጥም
ቀት ፡ ልትጠመቁ ፡ ትችላላችሁን ? አለ ። እንች
ላለን ፡ አሉት ። እርሱም ፡— ጽዋዬንስ ፡ ትጠጣ ፳፫
ላችሁ ፤ በቀኝና ፡ በግራ ፡ መቀመጥ ፡ ግን ፡ ከአ
ባቴ ፡ ዘንድ ፡ ለተዘጋጀላቸው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እኔ ፡
የምሰጥ ፡ አይደለሁም ፡ አላቸው ። አሥሩም ፡ ፳፬
ሰምተው ፡ በሁለቱ ፡ ወንድማማች ፡ ተቈጡ ።
ኢየሱስ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ጠርቶ ፡ እንዲህ ፡ ፳፭
አላቸው ፡— የአሕዛብ ፡ አለቆች ፡ እንዲገዙአ
ቸው ፡ ታላላቆቹም ፡ በላያቸው ፡ እንዲሠለጥኑ ፡
ታውቃላችሁ ። በእናንተስ ፡ እንዲህ ፡ አይደለም ፤ ፳፮
ነገር ፡ ግን ፡ ማንም ፡ ከእናንተ ፡ ታላቅ ፡ ሊሆን ፡
የሚወድ ፡ የእናንተ ፡ አገልጋይ ፡ ይሁን ፥ ከእ ፳፯
ናንተም ፡ ማንም ፡ ፊተኛ ፡ ሊሆን ፡ የሚወድ ፡
የእናንተ ፡ ባሪያ ፡ ይሁን ፤ እንዲሁም ፡ የሰው ፡ ፳፰
ልጅ ፡ ሊያገለግል ፡ ነፍሱንም ፡ ለብዙዎች ፡ ቤዛ ፡
ሊሰጥ ፡ እንጂ ፡ እንዲያገለግሉት ፡ አልመጣም ።

ከኢያሪኮም ፡ ሲወጡ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ተከተ ፳፱
ሉት ። እነሆም ፥ ሁለት ፡ ዕውሮች ፡ በመንገድ ፡ ፴
ዳር ፡ ተቀምጠው ፥ ኢየሱስ ፡ እንዲያልፍ ፡
በሰሙ ፡ ጊዜ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ የዳዊት ፡ ልጅ ፥
ማረን ፡ ብለው ፡ ጮኹ ። ሕዝቡም ፡ ዝም ፡ እን ፴፩
ዲሉ ፡ ገሠጹአቸው ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥
የዳዊት ፡ ልጅ ፥ ማረን ፡ እያሉ ፡ አብዝተው ፡
ጮኹ ። ኢየሱስም ፡ ቆሞ ፡ ጠራቸውና ፡— ምን ፡ ፴፪
ላደርግላችሁ ፡ ትወዳላችሁ ? አለ ። ጌታ ፡ ሆይ ፥ ፴፫
ዓይኖቻችን ፡ ይከፈቱ ፡ ዘንድ ፡ አሉት ። ኢየሱ ፴፬

፲፱ ። ፳፰ ፤ ሉቃ. ፳፪ ፡ ፴ ። ፴ ፤ ምዕ. ፳ ፡ ፲፮ ፤ ማር. ፲ ፡ ፴፩ ፤ ሉቃ. ፲፫ ፡ ፴ ።

፳ ። ፲፮ ፤ ምዕ. ፲፱ ፡ ፴ ። ፲፯—፲፱ ፤ ማር. ፲ ፡ ፴፪—፴፬ ፤ ሉቃ. ፲፰ ፡ ፴፩—፴፫ ። ፲፰ ፡ ፲፱ ፤ ምዕ. ፲፯ ፡ ፳፪ ። ፳—፳፰ ፤ ማር. ፲ ፡ ፴፭—፵፭ ። ፳፪ ፤ ምዕ. ፳፮ ፡ ፴፱ ፤ ዮሐ. ፲፰ ፡ ፲፩ ፤ ሉቃ. ፲፪ ፡ ፶ ። ፳፭—፳፰ ፤ ሉቃ. ፳፪ ፡ ፳፭—፳፯ ። ፳፰ ፤ ዮሐ. ፲፫ ፡ ፬ ፡ ፳ ፡ ፲፫—፲፭ ። ፳፱—፴፬ ፤ ማር. ፲ ፡ ፵፮—፶፪ ፤ ሉቃ. ፲፰ ፡ ፴፭—፵፫ ።

ስም ፡ አዘነላቸውና ፥ ዓይኖቻቸውን ፡ ዳሰሰ ፤ ወዲያውም ፡ አዩና ፡ ተከተሉት ።

ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ቀርበው ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ፋጌ ፡ ሲደርሱ ፥ ያንጊዜ ፡ ፪ ኢየሱስ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ሁለት ፡ ላከ ፥ እንዲህም ፡ አላቸው ፦ በፊታችሁ ፡ ወዳለችው ፡ መንደር ፡ ሂዱ ፥ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ የታሰረችን ፡ አህያ ፡ ውርንጫም ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ ታገኛላ ፫ ችሁ ፤ ፈትታችሁ ፡ አምጡልኝ ። ማንም ፡ አንዳች ፡ ቢላችሁ ፦ ለጌታ ፡ ያስፈልጉታል ፡ በሉ ፤ ወዲያውም ፡ ይሰዳቸዋል ።

፬፡፭ ለጽዮን ፡ ልጅ ፦ እነሆ ፥ ንጉሥሽ ፡ የዋህ ፡
ሆኖ ፡ በአህያ ፡ ላይና ፡ በአህያይቱ ፡ ግልገል ፡
በውርንጫይቱ ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ወደ ፡
አንቺ ፡ ይመጣል ፡ በሉአት ፡

ተብሎ ፡ በነቢይ ፡ የተነገረው ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ ፮ ይህ ፡ ሆነ ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ሄደው ፡ ኢየ ፯ ሱስ ፡ እንዳዘዛቸው ፡ አደረጉ ፤ አህያይቱንና ፡ ውርንጫዋንም ፡ አመጡለት ፥ ልብሳቸውንም ፡ ፰ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ጫኑ ፥ ተቀመጠባቸውም ። ከሕዝቡም ፡ እጅግ ፡ ብዙዎች ፡ ልብሳቸውን ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ አነጠፉ ፥ ሌሎችም ፡ ከዛፍ ፡ ጫፍ ፡ ጫፉን ፡ እየቈረጡ ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ ያነጥፉ ፡ ፱ ነበር ። የሚቀድሙትም ፡ ሕዝብ ፡ የሚከተሉትም ፦ ሆሣዕና ፡ ለዳዊት ፡ ልጅ ፤ በጌታ ፡ ስም ፡ የሚመጣ ፡ የተባረከ ፡ ነው ፤ ሆሣዕና ፡ በአርያም ፡ ፲ እያሉ ፡ ይጮኹ ፡ ነበር ። ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ መላው ፡ ከተማ ፦ ይህ ፡ ማን ፡ ነው ? ፲፩ ብሎ ፡ ተናወጠ ። ሕዝቡም ፦ ይህ ፡ ከገሊላ ፡ ናዝሬት ፡ የመጣ ፡ ነቢዩ ፡ ኢየሱስ ፡ ነው ፡ አሉ ።

፲፪ ኢየሱስም ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ ገባና ፡ በመቅደስ ፡ የሚሸጡትንና ፡ የሚገዙትን ፡ ሁሉ ፡ አወጣ ፥ የገንዘብ ፡ ለዋጮችንም ፡ ገበታዎች ፡ የርግብ ፡ ፲፫ ሻጮችንም ፡ ወንበሮች ፡ ገለበጠና ፦ ቤቴ ፡ የጸሎት ፡ ቤት ፡ ትባላለች ፡ ተብሎ ፡ ተጽፎአል ፥ እናንተ ፡ ግን ፡ የወንበዴች ፡ ዋሻ ፡ አደረጋችኋት ፡ አላቸው ።

፲፬ በመቅደስም ፡ ዕውሮችና ፡ አንካሶች ፡ ወደ ፡ ፲፭ እርሱ ፡ ቀረቡና ፡ ፈወሳቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ የካህናት ፡ አለቆችና ፡ ጻፎች ፡ ያደረገውን ፡ ድንቃ ድንቅ ፡ በመቅደስም ፦ ሆሣዕና ፡ ለዳዊት ፡ ልጅ ፡ እያሉ ፡ የሚጮኹትን ፡ ልጆች ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፥ ተቈ ፲፮ ጥተው ፦ እነዚህ ፡ የሚሉትን ፡ አትሰማምን ? አሉት ። ኢየሱስም ፦ እሰማለሁ ፤ ከሕፃናትና ፡ ከሚጠቡት ፡ አፍ ፡ ምስጋናን ፡ ለራስህ ፡ አዘጋጀህ ፡ የሚለውን ፡ ቃል ፡ ከቶ ፡ አላነበባችሁምን ? ፲፯ አላቸው ። ትቶአቸውም ፡ ከከተማ ፡ ወደ ፡ ቢታንያ ፡ ወጣ ፡ በዚያም ፡ አደረ ።

፲፰ ለማለዳም ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ሲመለስ ፡ ተራበ ። ፲፱ በመንገድም ፡ አጠገብ ፡ በለስ ፡ አይቶ ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ መጣ ፤ ከቅጠልም ፡ ብቻ ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ አላገኘባትምና ፦ ለዘላለሙ ፡ ፍሬ ፡ አይገኝብሽ ፡ አላት ። በለሲቱም ፡ ያንጊዜውን ፡ ደረቀች ። ፳ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ይህን ፡ አይተው ፦ በለሲቱ ፡ ያንጊዜውን ፡ እንዴት ፡ ደረቀች ? ብለው ፡ ተደነቁ ። ፳፩ ኢየሱስም ፡ መልሶ ፦ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ እምነት ፡ ቢኖራችሁ ፡ ባትጠራጠሩም ፥ በበለሲቱ ፡ እንደ ፡ ሆነበት ፡ ብቻ ፡ አታደርጉም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ይህን ፡ ተራራ ፡ እንኳ ፦ ተነቅለህ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ተወርወር ፡ ብትሉት ፡ ይሆናል ፤ ፳፪ አምናችሁም ፡ በጸሎት ፡ የምትለምኑትን ፡ ሁሉ ፡ ትቀበላላችሁ ፡ አላቸው ።

፳፫ ወደ ፡ መቅደስም ፡ ገብቶ ፡ ሲያስተምር ፡ የካህናት ፡ አለቆችና ፡ የሕዝብ ፡ ሽማግሎች ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀረቡና ፦ በምን ፡ ሥልጣን ፡ እነዚህን ፡ ታደርጋለህ ? ይህንስ ፡ ሥልጣን ፡ ማን ፡ ሰጠህ ? ፳፬ አሉት ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፦ እኔ ፡ ደግሞ ፡ አንዲት ፡ ነገር ፡ እጠይቃችኋለሁ ፤ እናንተም ፡ ያችን ፡ ብትነግሩኝ ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ እነዚህን ፡ በምን ፡ ሥልጣን ፡ እንዳደርግ ፡ እነግራችኋለሁ ፤ ፳፭ የዮሐንስ ፡ ጥምቀት ፡ ከወዴት ፡ ነበረች ? ከሰማይን ፡ ወይስ ፡ ከሰው ? አላቸው ። እነርሱም ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ሲነጋገሩ ፦ ከሰማይ ፡ ብንል ፦ እንኪያስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አላመናችሁበትም ? ይለናል ፤ ፳፮ ከሰው ፡ ግን ፡ ብንል ፥ ዮሐንስን ፡ ሁሉም ፡ እንደ ፡ ነቢይ ፡ ያዩታልና ፡ ሕዝቡን ፡ እንፈራለን ፡ አሉ ። ፳፯ ለኢየሱስም ፡ መልሰው ፦ አናውቅም ፡ አሉት ። እርሱም ፡ ደግሞ ፦ እኔም ፡ በምን ፡ ሥልጣን ፡ እነዚህን ፡ እንዳደርግ ፡ አልነግራችሁም ፡ አላቸው ።

፳፰ ነገር ፡ ግን ፡ ምን ፡ ይመስላችኋል ? አንድ ፡ ሰው ፡ ሁለት ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ፤ ወደ ፡ አንደኛው ፡ ቀርቦ ፦ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ዛሬ ፡ ሂድና ፡ በወይኔ ፡ አትክልት ፡ ሥራ ፡ አለው ። ፳፱ እርሱም ፡ መልሶ ፦ አልወድም ፡ አለ ፤ ኋላ ፡ ግን ፡ ተጸጸተና ፡ ሄደ ። ፴ ወደ ፡ ሁለተኛውም ፡ ቀርቦ ፡ እንዲሁ ፡ አለው ። እርሱም ፡ መልሶ ፦ እሺ ፡ ጌታዬ ፡ አለ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አልሄደም ። ፴፩ ከሁለቱ ፡ የአባቱን ፡ ፈቃድ ፡ ያደረገ ፡ ማን ፡ ነው ? ፊተኛው ፡ አሉት ። ኢየሱስ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ቀራጮችና ፡ ጋለሞቶች ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ በመግባት ፡ ይቀድሙአችኋል ። ፴፪ ዮሐንስ ፡ በጽድቅ ፡ መንገድ ፡ መጥቶላችሁ ፡ ነበርና ፥ አላመናችሁበትም ፤ ቀራጮችና ፡ ጋለሞቶች ፡ ግን ፡ አመኑበት ፤ እናንተም ፡ ይህን ፡ አይታችሁ ፡ ታምኑበት ፡ ዘንድ ፡ በኋላ ፡ ንስሐ ፡ አልገባችሁም ።

፴፫ ሌላ ፡ ምሳሌ ፡ ስሙ ። የወይን ፡ አትክልት ፡ የተ

፳፩ ። ፩—፱ ፤ ማር. ፲፩ ፥ ፩—፲ ፤ ሉቃ. ፲፱ ፥ ፳፱—፴፰ ፤ ዮሐ. ፲፪ ፥ ፲፪—፲፭ ። ፭ ፤ ዘካ. ፱ ፥ ፱ ። ፰ ፤ ፬ ነገሥ. ፱ ፥ ፲፫ ። ፱ ፤ መዝ. ፻፲፰ ፥ ፳፭ ፥ ፳፮ ። ፲ ፤ ዮሐ. ፲፪ ፥ ፲፱ ። ፲፪—፲፯ ፤ ማር. ፲፩ ፥ ፲፭—፲፱ ፤ ሉቃ. ፲፱ ፥ ፵፭—፵፰ ፤ ዮሐ. ፪ ፥ ፲፬—፲፮ ። ፲፫ ፤ ኢሳ. ፶፮ ፥ ፯ ፤ ኤር. ፯ ፥ ፲፩ ። ፲፮ ፤ መዝ. ፰ ፥ ፪ ። ፳፩ ፤ ማቴ. ፲፯ ፥ ፳ ። ፳፪ ፤ ማቴ. ፯ ፥ ፯ ። ፳፫—፳፯ ፤ ማር. ፲፩ ፥ ፳፯—፴፫ ፤ ሉቃ. ፳ ፥ ፩—፰ ። ፳፮ ፤ ማቴ. ፲፬ ፥ ፭ ። ፴፩ ፤ ሉቃ. ፯ ፥ ፳፱ ። ፴፪ ፤ ሉቃ. ፫ ፥ ፲፪ ። ፴፫—፵፮ ፤ ማር. ፲፪ ፥ ፩—፲፪ ፤ ሉቃ. ፳ ፥ ፱—፲፱ ፤ ኢሳ. ፭ ፥ ፩ ፤ ፪ ።

ነበረ ፡ ባለቤት ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ቅጥርም ፡ ቀጠረለት ÷ መጥመቂያም ፡ ማሰለት ÷ ግንብም ፡ ሠራና ፡ ለገበሬዎች ፡ አከራይቶ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ አገር ፡ ሄደ ።
፴፬ የሚያፈራበትም ፡ ጊዜ ፡ ሲቀርብ ÷ ፍሬውን ፡
፴፭ ሊቀበሉ ፡ ባሮቹን ፡ ወደ ፡ ገበሬዎች ፡ ላከ ። ገበሬዎቹም ፡ ባሮቹን ፡ ይዘው ፡ አንዱን ፡ ደበደቡት ፡ አንዱንም ፡ ገደሉት ፡ ሌላውንም ፡ ወገሩት ።
፴፮ ደግሞ ፡ ከፊተኞች ፡ የሚበዙ ፡ ሌሎች ፡ ባሮችን ፡
፴፯ ላከ ÷ እንዲሁም ፡ አደረጉባቸው ። በኋላ ፡ ግን ፡— ልጄንስ ፡ ያፍሩታል ፡ ብሎ ፡ ልጁን ፡ ላከባቸው ።
፴፰ ገበሬዎቹ ፡ ግን ፡ ልጁን ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡—ወራሹ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ኑ ፤ እንግደለውና ፡
፴፱ ርስቱን ፡ እናግኝ ፡ ተባባሉ ። ይዘውም ፡ ከወይኑ ፡
፵ አትክልት ፡ አወጡና ፡ ገደሉት ። እንግዲህ ፡ የወይኑ ፡ አትክልት ፡ ጌታ ፡ በሚመጣ ፡ ጊዜ ፡ በእነ
፵፩ ዚህ ፡ ገበሬዎች ፡ ምን ፡ ያደርግባቸዋል ? እነርሱም ፡— ክፉዎችን ፡ በክፉ ፡ ያጠፋቸዋል ÷ የወይኑንም ፡ አትክልት ፡ ፍሬውን ፡ በየጊዜው ፡ ለሚያስረክቡ ፡ ለሌሎች ፡ ገበሬዎች ፡ ይሰጠዋል ፡ አሉት ።
፵፪ ኢየሱስ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡—

ግንበኞች ፡ የናቁት ፡ ድንጋይ ÷ እርሱ ፡ የማዕዘን ፡ ራስ ፡ ሆነ ፤ ይህም ፡ ከጌታ ፡ ዘንድ ፡ ሆነ ÷ ለዓይኖቻችንም ፡ ድንቅ ፡ ነው ፡

የሚለውን ፡ ከቶ ፡ በመጽሐፍ ፡ አላነበባችሁምን ?
፵፫ ስለዚህ ፡ እላችኋለሁ ÷ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ከእናንተ ፡ ትወሰዳለች ፡ ፍሬዋንም ፡
፵፬ ለሚያደርግ ፡ ሕዝብ ፡ ትሰጣለች ። በዚህም ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ የሚወድቅ ፡ ይቀጠቀጣል ፤ ድንጋዩ ፡ ግን ፡ የሚወድቅበትን ፡ ሁሉ ፡ ይፈጨዋል ።
፵፭ የካህናት ፡ አለቆችና ፡ ፈሪሳውያንም ፡ ምሳሌዎቹን ፡ ሰምተው ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡
፵፮ አስተዋሉ ፤ ሊይዙትም ፡ ሲፈልጉት ፡ ሰሉ ፡ ሕዝቡ ፡ እንደ ፡ ነቢይ ፡ ስላዩት ፡ ፈሩአቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ ኢየሱስም ፡ መለሰ ፡ ደግሞም ፡ በምሳሌ ፡ ነገ
፪ ራቸው ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡— መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ለልጁ ፡ ሰርግ ፡ ያደረገ ፡ ንጉሥን ፡ ትመስ
፫ ላለች ። የታደሙትንም ፡ ወደ ፡ ሰርጉ ፡ ይጠሩ ፡ ዘንድ ፡ ባሮቹን ፡ ላከ ፡ ሊመጡም ፡ አልወደዱም ።
፬ ደግሞ ፡ ሌሎችን ፡ ባሮች ፡ ልኮ ፡— የታደሙትን ፡— እነሆ ÷ ድግሴን ፡ አዘጋጀሁ ÷ ኮርማዎቼና ፡ የሰቡት ፡ ከብቶቼ ፡ ታርደዋል ÷ ሁሉም ፡ ተዘጋጅቶአል ፤ ወደ ፡ ሰርጉ ፡ ኑ ፡ በሉአቸው ፡
፭ አለ ። እነርሱ ፡ ግን ፡ ቸል ፡ ብለው ፡ አንዱ ፡ ወደ ፡
፮ እርሻው ÷ ሌላውም ፡ ወደ ፡ ንግዱ ፡ ሄደ ፤ የቀሩትም ፡ ባሮቹን ፡ ይዘው ፡ አንገላቱአቸው ፡ ገደሉ
፯ አቸውም ። ንጉሡም ፡ ተቈጣ ÷ ጭፍሮቹንም ፡ ልኮ ፡ እነዚያን ፡ ገዳዮች ፡ አጠፋ ፤ ከተማቸውንም ፡ አቃጠለ ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ባሮቹን ፡— ሰርጉስ ፡ ተዘጋጅቶአል ÷ ነገር ፡ ግን ፡ የታደሙት ፡
፰ የማይገባቸው ፡ ሆኑ ፤ እንግዲህ ፡ ወደ ፡ መንገድ ፡ መተላለፊያ ፡ ሄዳችሁ ፡ ያገኛችሁትን ፡
፱ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ሰርጉ ፡ ጥሩ ፡ አለ ። እነዚያም ፡
፲ ባሮች ፡ ወደ ፡ መንገድ ፡ወጥተው ፡ ያገኙትን ፡ ሁሉ ፡ ክፉዎችንም ፡ በጎዎችንም ፡ ሰበሰቡ ፤ የሰርጉንም ፡ ቤት ፡ ተቀማጮች ፡ ሞሉት ።
፲፩ ንጉሡም ፡ የተቀመጡትን ፡ ለማየት ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ በዚያ ፡ የሰርግ ፡ ልብስ ፡ ያለበሰ ፡ አንድ ፡
፲፪ ሰው ፡ አየና ፡—ወዳጄ ፡ ሆይ ÷ የሰርግ ፡ ልብስ ፡ ሳትለብስ ፡ እንዴት ፡ ወደዚህ ፡ ገባህ ? አለው ፤
፲፫ እርሱም ፡ ዝም ፡ አለ ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ንጉሡ ፡ አገልጋዮቹን ፡—እጁንና ፡ እግሩን ፡ አስራችሁ ፡ በውጭ ፡ወዳለው ፡ ጨለማ ፡ አውጡት ፤ በዚያ ፡ ልቅሶና ፡ ጥርስ ፡ ማፋጨት ፡ ይሆናል ፡ አለ ።
፲፬ የተጠሩ ፡ ብዙዎች ÷ የተመረጡ ፡ ግን ፡ ጥቂቶች ፡ ናቸውና ።
፲፭ ስለዚህ ፡ ፈሪሳውያን ፡ ሄዱና ፡ እንዴት ፡ አድርገው ፡ በነገር ፡ እንዲያጠምዱት ፡ ተማከሩ ።
፲፮ ደቀ ፡ መዛሙርታቸውንም ፡ ከሄሮድስ ፡ ወገን ፡ ጋር ፡ ላኩበት ÷ እነርሱም ፡—መምህር ፡ ሆይ ÷ እውነተኛ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ በእውነትም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንገድ ፡ እንድታስተምር ፡ እናውቃለን ÷ ለማንምም ፡ አታደላም ÷ የሰውን ፡ ፊት ፡
፲፯ አትመለከትምና ፤ እንግዲህ ፡ ምን ፡ ይመስልሃል ? ንገረን ፤ ለቄሣር ፡ ግብር ፡ መስጠት ፡ ተፈቅዶአልን ፡ ወይስ ፡ አልተፈቀደም ? አሉት ።
፲፰ ኢየሱስም ፡ ክፋታቸውን ፡ አውቆ ፡—እናንተ ፡
፲፱ ግብዞች ÷ ስለ ፡ ምን ፡ ትፈትኑኛላችሁ ? የግብሩን ፡ ብር ፡ አሳዩኝ ፡ አለ ። እነርሱም ፡ ዲናር ፡
፳ አመጡለት ። እርሱም ፡—ይህች ፡ መልክ ፡ ጽሕ
፳፩ ፈቱስ ፡ የማን ፡ ናት ? አላቸው ። የቄሣር ፡ ነው ፡ አሉት ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡—እንኪያስ ፡ የቄሣርን ፡ ለቄሣር ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡
፳፪ አስረክቡ ፡ አላቸው ። ይህንም ፡ ሰምተው ፡ ተደነቁ ÷ ትተውትም ፡ ሄዱ ።
፳፫ በዚያን ፡ ቀን ፡—ትንሣኤ ፡ ሙታን ፡ የለም ፡ የሚሉ ፡ ሰዱቃውያን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀረቡ ÷
፳፬ እንዲህም ፡ ብለው ፡ ጠየቁት ፡— መምህር ፡ ሆይ ÷ ሙሴ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ልጅ ፡ ሳይወልድ ፡ ሲሞት ፡ ወንድሙ ፡ ሚስቱን ፡ አግብቶ ፡ ለወንድሙ ፡ ዘር ፡ ይተካ ፡ አለ ። ሰባት ፡ ወንድማማች ፡
፳፭ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ ነበሩ ፤ ፊተኛውም ፡ ሚስት ፡ አግብቶ ፡ሞተ ÷ ዘርም ፡ ስለሌለው ፡ ሚስቱን ፡ ለወንድሙ ፡ ተወለት ፤ እንዲሁ ፡ ደግሞ ፡ ሁለተኛው ፡
፳፮ ሦስተኛውም ÷ እስከ ፡ሰባተኛው ፡ ድረስ ። ከሁ
፳፯ ሉም ፡ በኋላ ፡ ሴቲቱ ፡ ሞተች ። ሁሉ ፡ አግብ
፳፰ ተዋታልና ፡ በትንሣኤ ፡ ቀንስ ፡ ከሰባቱ ፡ ለማናቸው ፡ ሚስት ፡ ትሆናለች ?
፳፱ ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— መጻሕፍትንና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ኃይል ፡ አታ

[illegible]

፴ ውቁምና ፡ ትስታላችሁ ። በትንሣኤስ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መላእክት ፡ በሰማይ ፡ ይሆናሉ

፴፩፡፴፪ እንጂ ፡ አያገቡም ፡ አይጋቡምም ። ስለ ፡ ትንሣኤ ፡ሙታን ፡ ግን ፡— እኔ ፡ የአብርሃም ፡ አምላክ ፡ የይስሐቅም ፡ አምላክ ፡ የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ ነኝ ፡ የሚል ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ የተባለውን ፡ አላነበባችሁምን? የሕያዋን ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የሙታን ፡

፴፫ አይደለም ። ሕዝቡም ፡ ይህን ፡ ሰምተው ፡ በትምህርቱ ፡ ተገረሙ ።

፴፬ ፈሪሳውያንም ፡ ሰዱቃውያንን ፡ዝም ፡ እንዳሰኛቸው ፡ በሰሙ ፡ጊዜ ፡ አብረው ፡ ተሰበሰቡ ።

፴፭ ከእነርሱም ፡ አንድ ፡ ሕግ ፡ አዋቂ ፡ሊፈትነው ፡—

፴፮ መምህር ፡ ሆይ ፥ ከሕግ ፡ ማናቸይቱ ፡ ትእዛዝ ፡

፴፯ ታላቅ ፡ ናት ? ብሎ ፡ ጠየቀው ። ኢየሱስም ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— ጌታ ፡ አምላክህን ፡ በፍጹም ፡ልብህ ፡ በፍጹም ፡ ነፍስህም ፡ በፍጹም ፡

፴፰ አሳብህም ፡ ውደድ ። ታላቂቱና ፡ ፊተኛይቱ ፡

፴፱ ትእዛዝ ፡ ይህች ፡ ናት ። ሁለተኛይቱም ፡ ይህችን ፡ትመስላለች ፥ እርስዋም ፡—ባልንጀራህን ፡

፵ እንደ ፡ ነፍስህ ፡ ውደድ ፡ የምትለው ፡ ናት ። በእነዚህ ፡ በሁለቱ ፡ ትእዛዛት ፡ ሕጉም ፡ ሁሉ ፡ ነቢያትም ፡ ተሰቅለዋል ።

፵፩፡፵፪ ፈሪሳውያንም ፡ ተሰብስበው ፡ ሳሉ ፥ ኢየሱስ ፡— ስለ ፡ ክርስቶስ ፡ ምን ፡ ይመስላችኋል ? የማንስ ፡ ልጅ ፡ ነው ? ብሎ ፡ ጠየቃቸው ። የዳ

፵፫፡፵፬ ዊት ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ አሉት ። እርሱም ፡— እንኪያስ ፡ ዳዊት ፡—

> ጌታ ፡ ጌታዬን ፡— ጠላቶችህን ፡ የእግርህ ፡ መረገጫ ፡ አስክደርግልህ ፡ ድረስ ፡ በቀኜ ፡ ተቀመጥ ፡ አለው ፡

ሲል ፡ እንዴት ፡ በመንፈስ ፡ ጌታ ፡ ብሎ ፡ ይጠ

፵፭ ራዋል ? ዳዊትስ ፡ ጌታ ፡ ብሎ ፡ ከጠራው ፥ እን

፵፮ ዴት ፡ ልጁ ፡ ይሆናል ? አላቸው ። አንድም ፡ ቃል ፡ በንኳ ፡ ይመልስለት ፡ ዘንድ ፡ የተቻለው ፡ የለም ፥ ከዚያ ፡ ቀንም ፡ ጀምሮ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ማንም ፡ ሊጠይቀው ፡ አልደፈረም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ኢየሱስ ፡ ለሕዝቡና ፡ ለደቀ ፡

፪ መዛሙርቱ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ነገራቸው ፡— ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያን ፡ በሙሴ ፡ ወንበር ፡ ተቀምጠ

፫ ዋል ። ስለዚህ ፡ ያዘዙአችሁን ፡ ሁሉ ፡ አድርጉ ፡ ጠብቁትም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ እየተናገሩ ፡ አያደር

፬ ጉትምና ፡ እንደ ፡ ሥራቸው ፡ አታድርጉ ። ከባድና ፡ አስቸጋሪ ፡ሸክም ፡ ተብትበው ፡ በሰው ፡ ትከሻ ፡ ይጭናሉ ፥ እነርሱ ፡ ግን ፡ በጣታቸው ፡

፭ ስንኳ ፡ ሊነኩት ፡ አይወዱም ። ለሰውም ፡ እንዲታዩ ፡ ሥራቸውን ፡ ሁሉ ፡ ያደርጋሉ ፤ ስለዚህ ፡ አሸንክታባቸውን ፡ ያሰፋሉ ፡ ዘርፋንም ፡ ያስረ

፮ ዝማሉ ፥ በምሳም ፡ የከበሬታ ፡ ስፍራ ፥ በምኵ

፯ ራብም ፡ የከበሬታ ፡ ወንበር ፥ በገበያም ፡ ሰላምታና ፡— መምህር ፡ ሆይ ፡ መምህር ፡ ሆይ ፡ ተብ

፰ ለው ፡ እንዲጠሩ ፡ ይወዳሉ ። እናንተ ፡ ግን ፡— መምህር ፡ ተብላችሁ ፡ አትጠሩ ፤ መምህራችሁ ፡ አንድ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ እናንተም ፡ ሁላችሁ ፡ ወንድ

፱ ማማች ፡ ናችሁ ። አባታችሁ ፡ አንዱ ፡ እርሱም ፡ የሰማዩ ፡ ነውና ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ማንንም ፡—

፲ አባት ፡ ብላችሁ ፡ አትጥሩ ። ሊቃችሁ ፡ አንድ ፡ እርሱም ፡ ክርስቶስ ፡ ነውና ፡— ሊቃውንት ፡

፲፩ ተብላችሁ ፡ አትጠሩ ። ከእናንተም ፡ የሚበል

፲፪ ጠው ፡ አገልጋያችሁ ፡ ይሆናል ። ራሱን ፡ ከፍ ፡ የሚያደርግ ፡ ሁሉ ፡ ይዋረዳል ፥ ራሱንም ፡ የሚያዋርድ ፡ ሁሉ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።

፲፫ እናንተ ፡ ግብዞች ፡ ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያን ፥ መንግሥተ ፡ ሰማያትን ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ ስለምት ዘጉ ፥ ወዮላችሁ ፤ እናንተ ፡ አትገቡም ፡ የሚገ

፲፬ ቡትንም ፡ እንዳይገቡ ፡ ትከለክላላችሁ ። እና ንተ ፡ ግብዞች ፡ ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያን ፥ በጸሎት ፡ ርዝመት ፡ እያመካኛችሁ ፡ የመበለቶችን ፡ቤት ፡ ስለምትበሉ ፥ ወዮላችሁ ፤ ስለዚህ ፡ የባሰ ፡ ፍርድ ፡

፲፭ ትቀበላላችሁ ። እናንተ ፡ ግብዞች ፡ ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያን ፥ አንድ ፡ ሰው ፡ ልታሳምኑ ፡ በባሕርና ፡ በደረቅ ፡ ስለምትዞሩ ፥ በሆነም ፡ ጊዜ ፡ ከእናንተ ፡ይልቅ ፡ ሁለት ፡ እጥፍ ፡ የባሰ ፡ የገሃነም ፡ ልጅ ፡ ስለምታደርጉት ፥ ወዮላችሁ ።

፲፮ እናንተ ፡— ማንም ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ የሚምል ፡ ምንም ፡ የለበትም ፤ ማንም ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ወርቅ ፡ የሚምል ፡ ግን ፡ በመሐላው ፡ ይያዛል ፡ የምትሉ ፥ ስውሮች ፡ መሪዎች ፥ ወዮ

፲፯ ላችሁ ። እናንተ ፡ ደንቆሮዎችና ፡ ስውሮች ፥ ማናቸው ፡ ይበልጣል ? ወርቁ ፡ ነውን ? ወይስ ፡

፲፰ ወርቁን ፡ የቀደሰው ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ? ደግሞም ፡— ማንም ፡ በመሠዊያው ፡ የሚምል ፡ ምንም ፡ የለበትም ፡ ማንም ፡ በላዩ ፡ ባለው ፡ መባ ፡ የሚምል ፡ ግን ፡ በመሐላው ፡ ይያዛል ፡ ትላላ

፲፱ ችሁ ። እናንተ ፡ ደንቆሮዎችና ፡ ዕውሮች ፥ ማናቸው ፡ ይበልጣል ? መባው ፡ ነውን ? ወይስ ፡

፳ መባውን ፡ የሚቀድሰው ፡ መሠዊያው ? እንግዲህ ፡ በመሠዊያው ፡ የሚምለው ፡ በእርሱና ፡

፳፩ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ባለው ፡ ሁሉ ፡ ይምላል ፤ በቤተ ፡ መቅደስም ፡ የሚምለው ፡ በእርሱና ፡ በእርሱ ፡

፳፪ በሚኖረው ፡ ይምላል ፤ በሰማይም ፡ የሚምለው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዙፋንና ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ በተቀመጠው ፡ ይምላል ።

፳፫ እናንተ ፡ ግብዞች ፡ ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያን ፥ ከእ

፳፪ ። ፴፪ ፤ ዘፀአ. ፫ ፥ ፮ ። [illegible] ማር. ፲፪ ፥ ፳፰ — [illegible] ሉቃ. ፲ ፥ ፳፯ ። [illegible] ዘዳግ. ፮ ፥ ፭ ። [illegible] ዘሌዋ. ፲፱ ፥ ፲፰ ። ፵፩ — ፵፭ ፤ ማር. ፲፪ ፥ ፴፭ — ፴፯ ፤ ሉቃ. ፳ ፥ ፵፩ — ፵፬ ። ፵፬ ፤ መዝ. ፻፲ ፥ ፩ ።

፳፫ ። [illegible] ሉቃ. ፳ ፥ ፵፭ ። [illegible] ሉቃ. ፲፩ ፥ ፵፮ ። [illegible] ዘኍል. ፲፭ ፥ ፴፰ ። [illegible] ማር. ፲፪ ፥ [illegible] ሉቃ. [illegible] [illegible] ሉቃ. [illegible] ማር. [illegible] ሉቃ. [illegible] ዘፀአ. [illegible] ዘሌዋ. [illegible] ሚክ. [illegible] ሉቃ. [illegible]

ዝሙድና ፡ ከእንስላል ፡ ከከሙንም ፡ አሥራት ፡
ስለምታወጡ ፥ ፍርድንና ፡ ምሕረትን ፡ ታማኝ
ነትንም ፥ በሕግ ፡ ያለውን ፡ ዋና ፡ ነገር ፡ ስለምት
ተዉ ፥ ወዮላችሁ ፤ ሌላውን ፡ ሳትተዉ ፡ ይህን ፡
፳፬ ልታደርጉ ፡ ይገባችሁ ፡ ነበር ። እናንተ ፡ ዕው
ሮች ፡ መሪዎች ፤ ትንኝን ፡ የምታጠሩ ፡ ግመል
ንም ፡ የምትውጡ ።

፳፭ እናንተ ፡ ግብዞች ፡ ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያን ፥
በውስጡ ፡ ቅሚያና ፡ ስስት ፡ ሞልቶ ፡ ሳለ ፡ የጽ
ዋውንና ፡ የወጭቱን ፡ ውጭ ፡ ስለምታጠሩ ፥
፳፮ ወዮላችሁ ። አንተ ፡ ዕውር ፡ ፈሪሳዊ ፥ ውጭው ፡
ደግሞ ፡ ጥሩ ፡ እንዲሆን ፡ አስቀድመህ ፡ የጽዋ
ውንና ፡ የወጭቱን ፡ ውስጡን ፡ አጥራ ።

፳፯ እናንተ ፡ ግብዞች ፡ ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያን ፥
በውጭ ፡ አምረው ፡ የሚታዩ ፡ በውስጥ ፡ ግን ፡
የሙታን ፡ አጥንት ፡ ርኵሰትም ፡ ሁሉ ፡ የተሞሉ ፡
በኖራ ፡ የተለሰኑ ፡ መቃብሮችን ፡ ስለምትመ
፳፰ ስሉ ፥ ወዮላችሁ ። እንዲሁ ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡
በውጭ ፡ ለሰው ፡ እንደ ፡ ጻድቃን ፡ ትታያላችሁ ፥
በውስጣችሁ ፡ ግን ፡ ግብዝነትና ፡ ዓመፀኝነት ፡
ሞልቶባችኋል ።

፳፱ እናንተ ፡ ግብዞች ፡ ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያን ፥ የነ
ቢያትን ፡ መቃብር ፡ ስለምትሠሩ ፡ የጻድቃንንም ፡
፴ መቃብር ፡ ስለምታስጌጡና ፦ በአባቶቻችን ፡
ዘመን ፡ ኖረን ፡ በሆነስ ፡ በነቢያት ፡ ደም ፡ ባልተ
ባበርናቸውም ፡ ነበር ፡ ስለምትሉ ፥ ወዮላችሁ ።
፴፩ እንግዲያስ ፡ የነቢያት ፡ ገዳዮች ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡
ሆናችሁ ፡ በራሳችሁ ፡ ላይ ፡ ትመሰክራላችሁ ።
፴፪ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ የአባቶቻችሁን ፡ መስፈሪያ ፡
፴፫ ሙሉ ። እናንተ ፡ እባቦች ፥ የእፉኝት ፡ ልጆች ፥
ከገሃነም ፡ ፍርድ ፡ እንዴት ፡ ታመልጣላችሁ ?
፴፬ ስለዚህ ፥ እነሆ ፥ ነቢያትንና ፡ ጥበበኞችን ፡ ጻፎ
ችንም ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ እልካለሁ ፤ ከእነርሱም ፡
ትገድላላችሁ ፡ ትሰቅሉማላችሁ ፥ ከእነርሱም ፡
በምኵራባችሁ ፡ ትገርፋላችሁ ፡ ከከተማም ፡
፴፭ ወደ ፡ ከተማ ፡ ታሳድዳላችሁ ፤ ከጻድቁ ፡ ከአቤል ፡
ደም ፡ ጀምሮ ፡ በቤተ ፡ መቅደስና ፡ በመሠዊያው ፡
መካከል ፡ እስከ ፡ ገደላችሁት ፡ እስከ ፡ በራክዩ ፡
ልጅ ፡ እስከ ፡ ዘካርያስ ፡ ደም ፡ ድረስ ፡ በምድር ፡
ላይ ፡ የፈሰሰው ፡ የጻድቅ ፡ ደም ፡ ሁሉ ፡ ይደር
፴፮ ስባችሁ ፡ ዘንድ ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ይህ ፡
ሁሉ ፡ በዚህ ፡ ትውልድ ፡ ላይ ፡ ይደርሳል ።

፴፯ ኢየሩሳሌም ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ፥ ነቢያትን ፡
የምትገድል ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ የተላኩትንም ፡
የምትወግር ፥ ዶሮ ፡ ጫጩቶችዋን ፡ ከክንፎ
ችዋ ፡ በታች ፡ እንደምትሰበስብ ፡ ልጆችሽን ፡
እሰበስብ ፡ ዘንድ ፡ ስንት ፡ ጊዜ ፡ ወደድሁ ! አል
፴፰ ወደዳችሁምም ። እነሆ ፥ ቤታችሁ ፡ የተፈታ ፡
፴፱ ሆኖ ፡ ይቀርላችኋል ። እላችኋለሁና ፥ በጌታ ፡
ስም ፡ የሚመጣ ፡ የተባረከ ፡ ነው ፡ እስክትሉ ፡
ድረስ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አታዩኝም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ ኢየሱስም ፡ ከመቅደስ ፡ ወጥቶ ፡ ሄደ ፥ ደቀ ፡
መዛሙርቱም ፡ የመቅደሱን ፡ ግንቦች ፡ ሊያሳ
፪ ዩት ፡ ቀረቡ ። እርሱ ፡ ግን ፡ መልሶ ፦ ይህን ፡
ሁሉ ፡ ታያላችሁን ? እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ድን
ጋይ ፡ በድንጋይ ፡ ላይ ፡ ሳይፈርስ ፡ በዚህ ፡ አይ
ቀርም ፡ አላቸው ።

፫ እርሱም ፡ በደብረ ፡ ዘይት ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፥
ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ለብቻቸው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀር
በው ፦ ንገረን ፥ ይህ ፡ መቼ ፡ ይሆናል ? የመም
ጣትህና ፡ የዓለም ፡ መጨረሻ ፡ ምልክቱስ ፡ ምን
፬ ድር ፡ ነው ? አሉት ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እን
ዲህ ፡ አላቸው ፦ ማንም ፡ እንዳያስታችሁ ፡
፭ ተጠንቀቁ ። ብዙዎች ፦ እኔ ፡ ክርስቶስ ፡ ነኝ ፡
እያሉ ፡ በስሜ ፡ ይመጣሉና ፤ ብዙዎችንም ፡ ያስ
፮ ታሉ ። ጦርንም ፡ የጦርንም ፡ ወሬ ፡ ትሰሙ ፡
ዘንድ ፡ አላችሁ ፤ ይህ ፡ ሊሆን ፡ ግድ ፡ ነውና ፡
ተጠበቁ ፥ አትደንግጡ ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ መጨረ
፯ ሻው ፡ ገና ፡ ነው ። ሕዝብ ፡ በሕዝብ ፡ ላይ ፡ መንግ
ሥትም ፡ በመንግሥት ፡ ላይ ፡ ይነሣልና ፥ ራብም ፡
ቸነፈርም ፡ የምድርም ፡ መናወጥ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡
፰ ስፍራ ፡ ይሆናል ፤ እነዚህም ፡ ሁሉ ፡ የምጥ ፡
ጣር ፡ መጀመሪያ ፡ ናቸው ።

፱ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ለመከራ ፡ አሳልፈው ፡ ይሰጡ
አችኋል ፡ ይገድሉአችሁማል ፥ ስለ ፡ ስሜም ፡
በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ የተጠላችሁ ፡ ትሆናላችሁ ።
፲ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ብዙዎች ፡ ይሰናከላሉ ፡ እርስ ፡
በርሳቸውም ፡ አሳልፈው ፡ ይሰጣጣሉ ፡ እርስ ፡
፲፩ በርሳቸውም ፡ ይጣላሉ ፤ ብዙ ፡ ሐሰተኞች ፡ ነቢ
፲፪ ያትም ፡ ይነሣሉ ፡ ብዙዎችንም ፡ ያስታሉ ፤ ከዓ
መፃም ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ የብዙ ፡ ሰዎች ፡ ፍቅር ፡
፲፫ ትቀዘቅዛለች ። እስከ ፡ መጨረሻ ፡ የሚጸና ፡ ግን ፡
፲፬ እርሱ ፡ ይድናል ። ለአሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ ምስክር ፡
እንዲሆን ፡ ይህ ፡ የመንግሥት ፡ ወንጌል ፡ በዓ
ለም ፡ ሁሉ ፡ ይሰበካል ፥ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ መጨ
ረሻው ፡ ይመጣል ።

፲፭ እንግዲህ ፡ በነቢዩ ፡ በዳንኤል ፡ የተባለውን ፡
የጥፋትን ፡ ርኵሰት ፡ በተቀደሰችው ፡ ስፍራ ፡
፲፮ ቆሞ ፡ ስታዩ ፥ አንባቢው ፡ ያስተውል ፥ በዚ
ያን ፡ ጊዜ ፡ በይሁዳ ፡ ያሉት ፡ ወደ ፡ ተራራዎች ፡
፲፯ ይሽሹ ፥ በሰገነትም ፡ ያለ ፡ በቤቱ ፡ ያለውን ፡
፲፰ ሊወስድ ፡ አይውረድ ፥ በእርሻም ፡ ያለ ፡ ልብ
ሱን ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ አይመ
፲፱ ለስ ። በዚያችም ፡ ወራት ፡ ለርጉዞችና ፡ ለሚ
፳ ያጠቡ ፡ ወዮላቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ ሽሽታችሁ ፡
በክረምት ፡ ወይም ፡ በሰንበት ፡ እንዳይሆን ፡

፳፫ ። ፳፭ ፤ ሉቃ ፡ ፲፩ ፥ ፴፱ ፤ ማር ፡ ፯ ፥ ፬ ። ፳፯ ፤ ሉቃ ፡ ፲፩ ፥ ፵፬ ። ፳፱—፴፩ ፤ ሉቃ ፡ ፲፩ ፥ ፵፯—፵፰ ። [illegible]

፳፬ ። [illegible]

፳፩ ጸልዩ ፤ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከዓለም ፡ መጀመሪያ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ያልሆነ ፡ እንግዲህም ፡ ከቶ ፡ የማይሆን ፡ ታላቅ ፡ መከራ ፡ ይሆናልና ። ፳፪ እነዚያ ፡ ቀኖችስ ፡ ባያጥሩ ፡ ሥጋ ፡ የለበስ ፡ ሁሉ ፡ ባልዳነም ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እነዚያ ፡ ቀኖች ፡ ስለ ፡ ተመረጡት ፡ ሰዎች ፡ ያጥራሉ ። ፳፫ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ማንም ፡— እነሆ ፥ ክርስቶስ ፡ ከዚህ ፡ አለ ፡ ወይም ፡— ከዚያ ፡ አለ ፡ ቢላችሁ ፡ አትመኑ ፤ ፳፬ ሐሰተኞች ፡ ክርስቶሶችና ፡ ሐሰተኞች ፡ ነቢያት ፡ ይነሣሉና ፥ ቢቻላቸውስ ፡ የተመረጡትን ፡ እንኳ ፡ እስኪያስቱ ፡ ድረስ ፡ ታላላቅ ፡ ምልክትና ፡ ድንቅ ፡ ያሳያሉ ። ፳፭ እነሆ ፥ አስቀድሜ ፡ ነገርኋችሁ ። ፳፮ እንግዲህ ፡— እነሆ ፥ በበረሀ ፡ ነው ፡ ቢሉአችሁ ፥ አትውጡ ፤ እነሆ ፥ በእልፍኝ ፡ ነው ፡ ቢሉአችሁ ፥ አትመኑ ፤ ፳፯ መብረቅ ፡ ከምሥራቅ ፡ ወጥቶ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ እንደሚታይ ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ መምጣት ፡ እንዲሁ ፡ ይሆናልና ፤ ፳፰ በድን ፡ ወዳለበት ፡ በዚያ ፡ አሞራዎች ፡ ይሰበሰባሉ ።

፳፱ ከዚያች ፡ ወራትም ፡ መከራ ፡ በኋላ ፡ ወዲያው ፡ ፀሐይ ፡ ይጨልማል ፥ ጨረቃም ፡ ብርሃንዋን ፡ አትሰጥም ፥ ከዋክብትም ፡ ከሰማይ ፡ ይወድቃሉ ፥ ፴ የሰማያትም ፡ ኃይላት ፡ ይናወጣሉ ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ምልክት ፡ በሰማይ ፡ ይታያል ፥ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ የምድር ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ ዋይ ፡ ዋይ ፡ ይላሉ ፥ የሰው ፡ ልጅንም ፡ በኃይልና ፡ በብዙ ፡ ክብር ፡ በሰማይ ፡ ደመና ፡ ሲመጣ ፡ ያዩታል ፤ ፴፩ መላእክቱንም ፡ ከታላቅ ፡ መለከት ፡ ድምፅ ፡ ጋር ፡ ይልካቸዋል ፥ ከሰማያትም ፡ ዳርቻ ፡ እስከ ፡ ዳርቻው ፡ ከአራቱ ፡ ነፋሳት ፡ ለእርሱ ፡ የተመረጡትን ፡ ይሰበስባሉ ።

፴፪ ምሳሌውንም ፡ ከበለስ ፡ ተማሩ ፤ ጫፍዋ ፡ ሲለሰልስ ፡ ቅጠልዋም ፡ ሲያቈጠቍጥ ፥ ያን ፡ ጊዜ ፡ ፴፫ በጋ ፡ እንደ ፡ ቀረበ ፡ ታውቃላችሁ ፤ እንዲሁ ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ስታዩ ፡ በደጅ ፡ ፴፬ እንደ ፡ ቀረበ ፡ እወቁ ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ይህ ፡ ሁሉ ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡ ይህ ፡ ትውልድ ፡ ፴፭ አያልፍም ። ሰማይና ፡ ምድር ፡ ያልፋሉ ፥ ቃሌ ፡ ግን ፡ አያልፍም ።

፴፮ ስለዚያች ፡ ቀንና ፡ ስለዚያች ፡ ሰዓት ፡ ግን ፡ ከአብ ፡ ብቻ ፡ በቀር ፡ የሰማይ ፡ መላእክትም ፡ ቢሆን ፡ ልጅም ፡ ቢሆን ፡ የሚያውቅ ፡ የለም ። ፴፯ የኖኅ ፡ ዘመን ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ መምጣት ፡ እንዲሁ ፡ ይሆናልና ። ፴፰ በዚያች ፡ ወራት ፡ ከጥፋት ፡ ውኃ ፡ በፊት ፥ ኖኅ ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ እስከገባበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፥ ሲበሉና ፡ ሲጠጡ ፡ ፴፱ ሲያገቡና ፡ ሲጋቡም ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፥ የጥፋት ፡ ውኃም ፡ መጥቶ ፡ ሁሉን ፡ እስከ ፡ ወሰደ ፡ ድረስ ፡ እንዳላወቁ ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ መምጣት ፡ ደግሞ ፡ ፵ እንዲሁ ፡ ይሆናል ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ በእርሻ ፡ ይሆናሉ ፤ አንዱ ፡ ይወሰዳል ፡ አንዱም ፡ ይቀራል ፤ ፵፩ ሁለት ፡ ሴቶች ፡ በወፍጮ ፡ ይፈጫሉ ፤ አንዲቱ ፡ ትወሰዳለች ፡ አንዲቱም ፡ ትቀራለች ። ፵፪ ጌታችሁ ፡ በምን ፡ ሰዓት ፡ እንዲመጣ ፡ አታውቁምና ፡ እንግዲህ ፡ ንቁ ።

፵፫ ያን ፡ ግን ፡ እወቁ ፤ ባለቤት ፡ ከሌሊቱ ፡ በየትኛው ፡ ክፍል ፡ ሌባ ፡ እንዲመጣ ፡ ቢያውቅ ፡ ኖሮ ፥ በነቃ ፡ ቤቱም ፡ ሊቈፈር ፡ ባልተወም ፡ ነበር ። ፵፬ ስለዚህ ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ተዘጋጅታችሁ ፡ ኑሩ ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ በማታስቡበት ፡ ሰዓት ፡ ይመጣልና ።

፵፭ እንኪያስ ፡ ምግባቸውን ፡ በጊዜው ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ጌታው ፡ በቤት ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ የሾመው ፡ ታማኝና ፡ ልባም ፡ ባሪያ ፡ ማን ፡ ነው ? ፵፮ ጌታው ፡ መጥቶ ፡ እንዲህ ፡ ሲያደርግ ፡ የሚያገኘው ፡ ያ ፡ ባሪያ ፡ ብፁዕ ፡ ነው ፤ ፵፯ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ባለው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ይሾመዋል ። ፵፰ ያ ፡ ክፉ ፡ ባሪያ ፡ ግን ፡— ጌታዬ ፡ እስኪመጣ ፡ ይዘገያል ፡ ብሎ ፡ በልቡ ፡ ቢያስብ ፥ ፵፱ ባልንጀሮቹን ፡ ባሮች ፡ ሊመታ ፡ ቢጀምር ፡ ከሰካሮችም ፡ ጋር ፡ ቢበላና ፡ ቢጠጣ ፥ ፶ የዚያ ፡ ባሪያ ፡ ጌታ ፡ ባልጠበቃት ፡ ቀን ፡ ባላወቃትም ፡ ሰዓት ፡ ይመጣል ፥ ፶፩ ከሁለትም ፡ ይሰነጥቀዋል ፥ እድሉንም ፡ ከግብዞች ፡ ጋር ፡ ያደርግበታል ፤ በዚያ ፡ ልቅሶና ፡ ጥርስ ፡ ማፋጨት ፡ ይሆናል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

፩ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ መብራታቸውን ፡ ይዘው ፡ ሙሽራውን ፡ ሊቀበሉ ፡ የወጡ ፡ አሥር ፡ ቈነጃጅትን ፡ ትመስላለች ። ፪ ከእነርሱም ፡ አምስቱ ፡ ሰነፎች ፡ አምስቱም ፡ ልባሞች ፡ ነበሩ ። ፫ ሰነፎቹ ፡ መብራታቸውን ፡ ይዘው ፡ ፬ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ዘይት ፡ አልያዙምና ፤ ልባሞቹ ፡ ግን ፡ ከመብራታቸው ፡ ጋር ፡ በማሰሮአቸው ፡ ዘይት ፡ ያዙ ። ፭ ሙሽራውም ፡ በዘገየ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ እንቅልፍ ፡ እንቅልፍ ፡ አላቸውና ፡ ተኙ ። ፮ እኩል ፡ ሌሊትም ፡ ሲሆን ፡— እነሆ ፥ ሙሽራው ፡ ይመጣል ፥ ትቀበሉት ፡ ዘንድ ፡ ውጡ ፡ የሚል ፡ ውካታ ፡ ሆነ ። ፯ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እነዚያ ፡ ቈነጃጅት ፡ ሁሉ ፡ ተነሡና ፡ መብራታቸውን ፡ አዘጋጁ ። ፰ ሰነፎቹም ፡ ልባሞቹን ፡— መብራታችን ፡ ሊጠፋብን ፡ ነው ፤ ከዘይታችሁ ፡ ስጡን ፡ አሉአቸው ። ፱ ልባሞቹ ፡ ግን ፡ መልሰው ፡— ምናልባት ፡ ለእኛና ፡ ለእናንተ ፡ ባይበቃስ ፤ ይልቅስ ፡ ወደሚሸጡት ፡ ሄዳችሁ ፡ ለራሳችሁ ፡ ግዙ ፡ አሉአቸው ። ፲ ሊገዙም ፡ በሄዱ ፡ ጊዜ ፡ ሙሽራው ፡ መጣ ፥ ተዘጋጅተው ፡ የነበሩትም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ሰርግ ፡ ገቡ ፥ ደጁም ፡ ተዘጋ ። ፲፩ በኋላም ፡ ደግሞ ፡ የቀሩቱ ፡ ቈነጃጅት ፡ መጡና ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ክፈትልን ፡ አሉ ። ፲፪ እርሱ ፡ ግን ፡ መልሶ ፡— እው

፳፬ ። ፳፩ ፡ ዳን. ፲፪ ፥ ፩ ። ፳፫ ፡ ሉቃ. ፲፯ ፥ ፳፫ ። ፳፯ ፡ ሉቃ. ፲፯ ፥ ፳፬ ። ፳፰ ፡ ኢዮብ ፴፱ ፥ ፴ ፡ ሉቃ. ፲፯ ፥ ፴፯ ። ፳፱ ፡ ኢሳ. ፲፫ ፥ ፲ ። ፴፭ ፡ ኢሳ. ፶፩ ፥ ፮ ፡ ፶ ፥ ፰ ። ፴፯—፴፱ ፡ ዘፍጥ. ፯ ፥ ፮ ፥ ፯ ፥ ፳፫ ፡ ሉቃ. ፲፯ ፥ ፳፯ ፡ ፳፯ ። ፵ ፡ ፵፩ ፡ ሉቃ. ፲፯ ፥ ፴፭ ፡ ፴፮ ። ፵፪ ፡ ም. ፳፭ ፥ ፲፫ ። ፵፫—፶፩ ፡ ሉቃ. ፲፪ ፥ ፴፱—፵፮ ። ፶፩ ፡ ሙሴ. ፰ ፥ ፲፪ ።
፳፭ ። ፲—፲፪ ፡ ሉቃ. ፲፫ ፥ ፳፭—፳፯ ።

፲፫ ነት ፡ አላችኋለሁ ፥ አላውቃችሁም ፡ አለ ። ቀኒቱ ንና ፡ ሰዓቲቱን ፡ አታውቁምና ፡ እንግዲህ ፡ ንቁ ።

፲፬ ወደ ፡ ሌላ ፡ አገር ፡ የሚሄድ ፡ ሰው ፡ ባሮቹን ፡ ጠርቶ ፡ ያለውን ፡ ገንዘብ ፡ እንደ ፡ ሰጣቸው ፡ እን ፲፭ ዲሁ ፡ ይሆናልና ፤ ለእያንዳንዱ ፡ እንደ ፡ ዓቅሙ ፥ ለአንዱ ፡ አምስት ፡ መክሊት ፡ ለአንዱ ፡ ሁለት ፡ ለአንዱም ፡ አንድ ፡ ሰጠና ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ አገር ፡ ፲፮ ወዲያው ፡ ሄደ ። አምስት ፡ መክሊትም ፡ የተቀበ ለው ፡ ሄዶ ፡ ነገደበት ፡ ሌላም ፡ አምስት ፡ አተ ፲፯ ረፈ ፤ እንዲሁም ፡ ሁለት ፡ የተቀበለው ፡ ሌላ ፡ ፲፰ ሁለት ፡ አተረፈ ። አንድ ፡ የተቀበለው ፡ ግን ፡ ሄዶ ፡ ምድርን ፡ ቈፈረና ፡ የጌታውን ፡ ገንዘብ ፡ ፲፱ ቀበረ ። ከብዙ ፡ ዘመንም ፡ በኋላ ፡ የእነዚያ ፡ ባሮች ፡ ፳ ጌታ ፡ መጣና ፡ ተቈጣጠራቸው ። አምስት ፡ መክ ሊት ፡ የተቀበለውም ፡ ቀረበና ፡ ሌላ ፡ አምስት ፡ መክሊት ፡ አስረክቦ ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፤ አምስት ፡ መክሊት ፡ ሰጥተኸኝ ፡ ነበር ፤ እነሆ ፥ ሌላ ፡ አም ፳፩ ስት ፡ መክሊት ፡ አተረፍሁበት ፡ አለ ። ጌታ ውም ፦ መልካም ፥ አንተ ፡ በጎ ፡ ታማኝም ፡ ባሪያ ፤ በጥቂቱ ፡ ታምነሃል ፥ በብዙ ፡ እሾምሃ ፳፪ ለሁ ፤ ወደ ፡ ጌታህ ፡ ደስታ ፡ ግባ ፡ አለው ። ሁለት ፡ መክሊትም ፡ የተቀበለው ፡ ደግሞ ፡ ቀርቦ ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ሁለት ፡ መክሊት ፡ ሰጥተኸኝ ፡ ነበር ፤ እነሆ ፥ ሌላ ፡ ሁለት ፡ መክሊት ፡ አተረፍ ፳፫ ሁበት ፡ አለ ። ጌታውም ፦ መልካም ፥ አንተ ፡ በጎ ፡ ታማኝም ፡ ባሪያ ፤ በጥቂቱ ፡ ታምነሃል ፥ በብዙ ፡ እሾምሃለሁ ፤ ወደ ፡ ጌታህ ፡ ደስታ ፡ ግባ ፡ ፳፬ አለው ። አንድ ፡ መክሊትም ፡ የተቀበለው ፡ ደግሞ ፡ ቀርቦ ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ከልዘራህበት ፡ የምታጭድ ፡ ካልበተንህበትም ፡ የምትሰበስብ ፡ ፳፭ ጨካኝ ፡ ሰው ፡ መሆንህን ፡ አውቃለሁ ፡ ፈራ ሁም ፡ ሄጄም ፡ መክሊትህን ፡ በምድር ፡ ቀበር ፳፮ ሁት ፤ እነሆ ፥ መክሊትህ ፡ አለህ ፡ አለ ። ጌታ ውም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፦ አንተ ፡ ክፉና ፡ ሃኬተኛ ፡ ባሪያ ፥ ካልዘራሁበት ፡ እንዳጭድ ፡ ካልበተንሁበትም ፡ እንድሰበስብ ፡ ታውቃለህን ? ፳፯ በስለዚህ ፡ ገንዘቤን ፡ ለለዋጮች ፡ አደራ ፡ ልትሰ ጠው ፡ ይገባህ ፡ ነበር ፥ እኔም ፡ መጥቼ ፡ ያለ ፳፰ ኝን ፡ ከትርፉ ፡ ጋር ፡ እወስደው ፡ ነበር ። ስለዚህ ፡ መክሊቱን ፡ ውሰዱበት ፡ አሥር ፡ መክሊትም ፡ ፳፱ ላለው ፡ ስጡት ፤ ላለው ፡ ሁሉ ፡ ይሰጠዋልና ፡ ይበዛለትማል ፤ ከሌለው ፡ ግን ፡ ያው ፡ ያለው ፡ ፴ እንኳ ፡ ይወሰድበታል ። የማይጠቅመውንም ፡ ባሪያ ፡ በውጭ ፡ ወዳለው ፡ ጨለማ ፡ አውጡት ፤ በዚያ ፡ ልቅሶና ፡ ጥርስ ፡ ማፋጨት ፡ ይሆናል ።

፴፩ የሰው ፡ ልጅ ፡ በክብሩ ፡ በሚመጣበት ፡ ጊዜ ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ቅዱሳን ፡ መላእክት ፡ ሁሉ ፥ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በክብሩ ፡ ዙፋን ፡ ይቀመጣል ፤ ፴፪ አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ይሰበሰባሉ ፤ እረኛም ፡ በጎቹን ፡ ከፍየሎች ፡ እንደሚለይ ፡ እርስ ፡ በር ፴፫ ሳቸው ፡ ይለያቸዋል ፥ በጎችን ፡ በቀኙ ፡ ፍየሎ ፴፬ ችንም ፡ በግራው ፡ ያቆማቸዋል ። ንጉሡም ፡ በቀኙ ፡ ያሉትን ፡ እንዲህ ፡ ይላቸዋል ፦ እናንተ ፡ የአባቴ ፡ ቡሩካን ፥ ኑ ፤ ዓለም ፡ ከተፈጠረበት ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ የተዘጋጀላችሁን ፡ መንግሥት ፡ ፴፭ ውረሱ ። ተርቤ ፡ አብልታችሁኛልና ፥ ተጠ ምቼ ፡ አጠጥታችሁኛልና ፥ እንግዳ ፡ ሆኜ ፡ ተቀ ፴፮ ብላችሁኛልና ፥ ታርዤ ፡ አልብሳችሁኛልና ፥ ታምሜ ፡ ጠይቃችሁኛልና ፥ ታስሬ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ፴፯ መጥታችኋልና ። ጻድቃንም ፡ መልሰው ፡ ይሉ ታል ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ተርበህ ፡ አይተን ፡ መቼ ፡ አበላንህስ ? ወይስ ፡ ተጠምተህ ፡ አይተን ፡ መቼ ፡ ፴፰ አጠጣንህ ? እንግዳ ፡ ሆነህስ ፡ አይተን ፡ መቼ ፡ ተቀበልንህ ? ወይስ ፡ ታርዘህ ፡ አይተን ፡ መቼ ፡ ፴፱ አለበስንህ ? ወይስ ፡ ታመህ ፡ ወይስ ፡ ታስረህ ፡ ፵ አይተን ፡ መቼ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ መጣን ? ንጉሡም ፡ መልሶ ፦ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ከሁሉ ፡ ከሚያንሱ ፡ ከእነዚህ ፡ ወንድሞቼ ፡ ለአንዱ ፡ እንኳ ፡ ስላ ደረጋችሁት ፡ ለእኔ ፡ አደረጋችሁት ፡ ይላቸዋል ። ፵፩ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በግራው ፡ ያሉትን ፡ ደግሞ ፡ ይላቸዋል ፦ እናንተ ፡ ርጉማን ፥ ለሰይጣንና ፡ ለመላእክቱ ፡ ወደ ፡ ተዘጋጀ ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ፵፪ እሳት ፡ ከእኔ ፡ ሂዱ ። ተርቤ ፡ አላበላችሁኝምና ፥ ፵፫ ተጠምቼ ፡ አላጠጣችሁኝምና ፥ እንግዳ ፡ ሆኜ ፡ አልተቀበላችሁኝምና ፥ ታርዤ ፡ አላለበሳችሁ ኝምና ፥ ታምሜ ፡ ታስሬም ፡ አልጠየቃችሁኝ ፵፬ ምና ። እነርሱ ፡ ደግሞ ፡ ይመልሱና ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ተርበህ ፡ ወይስ ፡ ተጠምተህ ፡ ወይስ ፡ እንግዳ ፡ ሆነህ ፡ ወይስ ፡ ታርዘህ ፡ ወይስ ፡ ታመህ ፡ ወይስ ፡ ታስረህ ፡ መቼ ፡ አይተን ፡ አላገለገልን ፵፭ ህም ? ይሉታል ። ያን ፡ ጊዜ ፦ እውነት ፡ እላች ኋለሁ ፥ ከሁሉ ፡ ከሚያንሱ ፡ ከእነዚህ ፡ ለአንዱ ፡ በላላደረጋችሁት ፡ ለእኔ ፡ ደግሞ ፡ አላደረጋችሁ ፵፮ ትም ፡ ብሎ ፡ ይመልስላቸዋል ። እነዚያም ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ቅጣት ፥ ጻድቃን ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ይሄዳሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩ ኢየሱስም ፡ እነዚህን ፡ ቃሎች ፡ ሁሉ ፡ በፈ ፪ ጸመ ፡ ጊዜ ፥ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፦ ከሁለት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ፋሲካ ፡ እንዲሆን ፡ታውቃላችሁ ፥ የሰው ፡ ልጅም ፡ ሊሰቀል ፡ አልፎ ፡ ይሰጣል ፡ አለ ።

፫ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የካህናት ፡ አለቆች ፡ የሕዝብም ፡ ሽማግሎች ፡ ቀያፋ ፡ በሚባለው ፡ በሊቀ ፡ ካህ ፬ ናቱ ፡ ግቢ ፡ ተሰበሰቡ ፥ ኢየሱስንም ፡ በተንኰል ፡ ፭ ሊያበይዙት ፡ ሊገድሉትም ፡ ተማከሩ ፤ ነገር ፡ ግን ፦ በሕዝቡ ፡ ሁከት ፡ እንዳይነሣ ፡ በበዓል ፡ አይሁን ፡ አሉ ።

፮ ኢየሱስም ፡ በቢታንያ ፡ በለምጻሙ ፡ በስምዖን

፳፭ ። [illegible]

፳፮ ። [illegible]

፯ ፡ ያን ፡ ቤት ፡ ሳለ ፤ አንዲት ፡ ሴት ፡ ዋጋው ፡ እጅግ ፡ የበዛ ፡ ሽቱ ፡ የሞላው ፡ የአልባስጥሮስ ፡ ብልቃጥ ፡ ይዛ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀረበች ፡ በማዕድም ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ አፈሰሰችው ።
፰ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ይህን ፡ አይተው ፡ ተቈ
፱ ፡ ጡና ፦ ይህ ፡ ጥፋት ፡ ለምንድር ፡ ነው ? ይህ ፡ ቡብዙ ፡ ዋጋ ፡ ተሽጦ ፡ ለድሆች ፡ ሊሰጥ ፡ ይቻል ፡
፲ ፡ ነበርና ፡ አሉ ። ኢየሱስም ፡ ይህን ፡ አውቆ ፡ እን ዲህ ፡ አላቸው ፦ መልካም ፡ ሥራ ፡ ሠርታልኛለ ችና ፡ ሴቲቱን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ታደክሙአታላችሁ ?
፲፩ ፡ ድሆች ፡ ሁልጊዜ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይኖራሉና ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ሁልጊዜ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ አልኖርም ፤
፲፪ ፡ እርስዋ ፡ ይህን ፡ ሽቱ ፡ በሰውነቴ ፡ ላይ ፡ አፍስሳ ፡
፲፫ ፡ ለመቃብሬ ፡ አደረገች ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ፤ ይህ ፡ ወንጌል ፡ በዓለም ፡ ሁሉ ፡ በማናቸውም ፡ ስፍራ ፡ በሚሰበክበት ፡ እርስዋ ፡ ያደረገችው ፡ ደግሞ ፡ ለእርስዋ ፡ መታሰቢያ ፡ እንዲሆን ፡ ይነገራል ።

፲፬ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የአስቆሮቱ ፡ ይሁዳ ፡ የሚባለው ፡ ከአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ አንዱ ፡ ወደ ፡ ካህናት ፡
፲፭ ፡ አለቆች ፡ ሄዶ ፦ ምን ፡ ልትሰጡኝ ፡ ትወዳላችሁ ፡ እኔም ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣችኋለሁ ? አነር
፲፮ ፡ ሉም ፡ ሠላሳ ፡ ብር ፡ መዘኑለት ። ከዚያችም ፡ ሰዓት ፡ ጀምሮ ፡ አሳልፎ ፡ ሊሰጠው ፡ ምቹ ፡ ጊዜ ፡ ይሻ ፡ ነበር ።

፲፯ ፡ ለቂጣው ፡ በዓል ፡ በመጀመሪያ ፡ ቀን ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡ ቀርበው ፦ ፋሲካን ፡ ትበላ ፡ ዘንድ ፡ ወዴት ፡ ልናሰናዳልህ ፡ ትወ
፲፰ ፡ ዳለህ ? አሉት ። እርሱም ፦ ወደ ፡ ከተማ ፡ ከአ ንዱ ፡ ዘንድ ፡ ሄዳችሁ ፦ መምህር ፦ ጊዜዬ ፡ ቀርቦአል ፤ ከደቀ ፡ መዛሙርቴ ፡ ጋር ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ ፋሲካን ፡ አደርጋለሁ ፡ ይላል ፡ በሉት ፡
፲፱ ፡ አለ ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ኢየሱስ ፡ እንዳዘዛ ቸው ፡ አደረጉ ፡ ፋሲካንም ፡ አሰናዱ ።

፳ ፡ በመሸም ፡ ጊዜ ፡ ከአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ደቀ ፡ መዛ
፳፩ ፡ ሙርቱ ፡ ጋር ፡ በማዕድ ፡ ተቀመጠ ። ሲበሉም ፦ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፤ ከእናንተ ፡ አንዱ ፡ እኔን ፡
፳፪ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣል ፡ አለ ። እጅግም ፡ አዝነው ፡ እያንዳንዱ ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፤ እኔ ፡ እሆንን ? ይሉት ፡
፳፫ ፡ ጀመር ። እርሱም ፡ መልሶ ፦ ከእኔ ፡ ጋር ፡ እጁን ፡ በወጭቱ ፡ ያጠለቀ ፤ እኔን ፡ አሳልፎ ፡ የሚሰጥ ፡
፳፬ ፡ እርሱ ፡ ነው ። የሰው ፡ ልጅስ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ይሄዳል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ አልፎ ፡ ለሚሰጥበት ፡ ለዚያ ፡ ሰው ፡ ወዮለት ፤ ያ ፡ ሰው ፡ ባልተወለደ ፡ ይሻለው ፡ ነበር ፡ አለ ።
፳፭ ፡ አሳልፎ ፡ የሚሰጠው ፡ ይሁዳም ፡ መልሶ ፦ መምህር ፡ ሆይ ፤ እኔ ፡ እሆንን ? አለ ፤ አንተ ፡ አልህ ፡ አለው ።

፳፮ ፡ ሲበሉም ፡ ኢየሱስ ፡ እንጀራን ፡ አንሥቶ ፡ ባረከ ፡ ቈርሶም ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ሰጠና ፦ እንካችሁ ፤ ብሉ ፤ ይህ ፡ ሥጋዬ ፡ ነው ፡ አለ ።
፳፯ ፡ ጽዋንም ፡ አንሥቶ ፡ አመስግኖም ፡ ሰጣቸው ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦ ሁላችሁ ፡ ከእርሱ ፡ ጠጡ ፤
፳፰ ፡ ስለ ፡ ብዙዎች ፡ ስኃጢአት ፡ ይቅርታ ፡ የሚፈስ ፡
፳፱ ፡ የአዲስ ፡ ኪዳን ፡ ደሜ ፡ ይህ ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፤ በአባቴ ፡ መንግሥት ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ከዚህ ፡ ከወይን ፡ ፍሬ ፡ አዲሱን ፡ እስከም ጠጣበት ፡ እስከዚያ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ከዛሬ ፡ ጀምሬ ፡ አልጠጣውም ።

፴ ፡ መዝሙርም ፡ ከዘመሩ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡
፴፩ ፡ ዘይት ፡ ወጡ ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ኢየሱስ ፦ በዚች ፡ ሌሊት ፡ ሁላችሁ ፡ በእኔ ፡ ትሰናከላላችሁ ፤ እረኛውን ፡ እመታለሁ ፡ የመንጋውም ፡ በጎች ፡
፴፪ ፡ ይበተናሉ ፡ የሚል ፡ ተጽፎአልና ፤ ከተነሣሁ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ እቀድማችኋለሁ ፡ አላ
፴፫ ፡ ቸው ። ጴጥሮስም ፡ መልሶ ፦ ሁሉም ፡ በአ ንተ ፡ ቢሰናከሉ ፡ እኔ ፡ ከቶ ፡ አልሰናከልም ፡
፴፬ ፡ አለው ። ኢየሱስ ፦ እውነት ፡ እልሃለሁ ፤ በዚች ፡ ሌሊት ፡ ዶሮ ፡ ሳይጮኽ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ትክደ
፴፭ ፡ ኛለህ ፡ አለው ። ጴጥሮስ ፦ ከአንተ ፡ ጋር ፡ መሞት ፡ እንኳ ፡ የሚያስፈልገኝ ፡ ቢሆን ፤ ከቶ ፡ አልክድህም ፡ አለው ። ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ሁሉ ፡ ደግሞ ፡ እንደዚሁ ፡ አሉ ።

፴፮ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ኢየሱስ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ጌቴሴማኒ ፡ ወደምትባል ፡ ስፍራ ፡ መጣ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱንም ፦ ወዲያ ፡ ሄጄ ፡ በጸልይ ፡ ሳለ ፡
፴፯ ፡ በዚህ ፡ ተቀመጡ ፡ አላቸው ። ጴጥሮስንም ፡ ሁለ ቱንም ፡ የዘብዴዎስን ፡ ልጆች ፡ ወሰዶ ፡ ሊያዝን ፡
፴፰ ፡ ሊተክዝም ፡ ጀመር ። ነፍሴ ፡ እስከ ፡ ሞት ፡ ድረስ ፡ እጅግ ፡ አዘነች ፤ በዚህ ፡ ቆዩ ፡ ከእኔም ፡ ጋር ፡
፴፱ ፡ ትጉ ፡ አላቸው ። ጥቂትም ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ በፊቱ ፡ ወደቀና ፡ ሲጸልይ ፦ አባቴ ፤ ቢቻልስ ፤ ይህች ፡ ጽዋ ፡ ከእኔ ፡ ትለፍ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አንተ ፡ እንደምትወድ ፡ ይሁን ፡ እንጂ ፡
፵ ፡ እኔ ፡ እንደምወድ ፡ አይሁን ፡ አለ ። ወደ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ መጣ ፤ ተኝተውም ፡ አገኛቸ ውና ፡ ጴጥሮስን ፦ እንዲሁም ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ አንዲት ፡ ሰዓት ፡ በንኳ ፡ ልትተጉ ፡ አልቻላችሁ
፵፩ ፡ ምን ? ወደ ፡ ፈተና ፡ እንዳትገቡ ፡ ትጉና ፡ ጸልዩ ፤ መንፈስስ ፡ ተዘጋጅታለች ፡ ሥጋ ፡ ግን ፡ ደካማ ፡
፵፪ ፡ ነው ፡ አለው ። ደግሞ ፡ ሁለተኛ ፡ ሄዶ ፡ ጸለየና ፦ አባቴ ፤ ይህች ፡ ጽዋ ፡ ሳልጠጣት ፡ ታልፍ ፡ ዘንድ ፡ የማይቻል ፡ እንደ ፡ ሆነ ፤ ፈቃድህ ፡ ትሁን ፡ አለ ።
፵፫ ፡ ደግሞም ፡ መጥቶ ፡ ዓይኖቻቸው ፡ በእንቅልፍ ፡
፵፬ ፡ ከብደው ፡ ነበርና ፡ ተኝተው ፡ አገኛቸው ። ደግ ሞም ፡ ትቶአቸው ፡ ሄደ ፤ ሦስተኛም ፡ ያንኑ ፡

፳፮ ። ፲፭ ፤ ዘካ. ፲፩ ÷ ፲፪ ። ፲፬—፲፮ ፤ ማር. ፲፬ ÷ ፲ ፡ ፲፩ ፤ ሉቃ. ፳፪ ÷ ፫—፮ ። ፲፯ ፤ ዮሐ. ፲፫ ÷ ፳፪ ። ፲፯—፲፱ ፤ ዘፀአ. ፲፪ ÷ ፲፰ ፤ ማር. ፲፬ ÷ ፲፪—፲፮ ፤ ሉቃ. ፳፪ ÷ ፯—፲፫ ። ፳፬ ፤ ዮሐ. ፮ ÷ ፱ ። ፳—፳፬ ፤ ማር. ፲፬ ÷ ፲፯—፳፩ ፤ ሉቃ. ፳፪ ÷ ፲፬ ፡ ፳፩—፳፫ ። ፳፩—፳፭ ፤ ዮሐ. ፲፫÷፳፩—፳፮ ። ፳፫ ፤ ዮሐ. ፲፫÷፲፰ ። ፳፮—፳፱ ፤ ማር. ፲፬÷፳፪—፳፭ ፤ ሉቃ. ፳፪÷፲፱—፳ ፤ ፩ ቆሮ. ፲፩ ÷ ፳፫—፳፭ ። ፳፰ ፤ ዘፀአ. ፳፬÷፰ ፤ ኤር. ፴፩ ÷ ፴፩ ። ፴—፴፭ ፤ ማር. ፲፬÷፳፮—፴፩ ፤ ሉቃ. ፳፪ ÷ ፴፱ ፤ ዮሐ. ፲፰ ÷ ፩ ። ፴፩ ፤ ዘካ. ፲፫ ÷ ፯ ፤ ዮሐ. ፲፮ ÷ ፴፪ ። ፴፪ ፤ ም. ፳፰ ÷ ፯ ። ፴፬ ፤ ሉቃ. ፳፪÷፴፬ ፤ ዮሐ. ፲፫ ÷ ፴፰ ። ፴፭ ፤ ሉቃ. ፳፪ ÷ ፴፫ ፤ ዮሐ. ፲፫÷፴፯ ። ፴፮—፵፮ ፤ ማር. ፲፬÷፴፪—፵፪ ፤ ሉቃ. ፳፪÷፵—፵፮ ። ፴፰ ፤ ዮሐ. ፲፪÷፳፯ ። ፴፱ ፤ ም. ፳÷፳፪ ።

ቃል፡ደግሞ፡ጸለየ። ፵፭ ከዚያ፡ወዲያ፡ወደ፡ደቀ፡መዛሙርቱ፡መጥቶ፡— እንግዲህስ፡ተኙ፡ዕረፉም፤ እነሆ፤ ሰዓቲቱ፡ቀርባለች፡የሰው፡ልጅም፡በኃጢአተኞች፡እጅ፡አልፎ፡ይሰጣል። ፵፮ ተነሡ፤ እንሂድ፤ እነሆ፡አሳልፎ፡የሚሰጠኝ፡ቀርቦአል፡አላቸው።

፵፯ ይህንም፡ገና፡ሲናገር፤ እነሆ፤ ከአሥራ፡ሁለቱ፡አንዱ፡ይሁዳ፡መጣ፤ ከእርሱም፡ጋር፡ብዙ፡ሕዝብ፡ሰይፍና፡ጐመድ፡ይዘው፡ከካህናት፡አለቆችና፡ከሕዝቡ፡ሽማግሎች፡ዘንድ፡መጡ። ፵፰ አሳልፎ፡የሚሰጠውም፡— የምስመው፡እርሱ፡ነው፤ ያዙት፡ብሎ፡ምልክት፡ሰጥቶአቸው፡ነበር። ፵፱ ወዲያውም፡ወደ፡ኢየሱስ፡ቀረበና፡— መምህር፡ሆይ፤ ሰላም፡ለአንተ፡ይሁን፡ብሎ፡ሳመው። ፶ ኢየሱስም፡— ወዳጄ፡ሆይ፤ ለምን፡ነገር፡መጣህ? አለው። በዚያን፡ጊዜ፡ቀረቡ፡እጃቸውንም፡በኢየሱስ፡ላይ፡ጭነው፡ያዙት። ፶፩ እነሆም፤ ከኢየሱስ፡ጋር፡ከነበሩት፡አንዱ፡እጁን፡ዘርግቶ፡ሰይፉን፡መዘዘና፡የሊቀ፡ካህናቱን፡ባሪያ፡መትቶ፡ጆሮውን፡ቈረጠው። ፶፪ በዚያን፡ጊዜ፡ኢየሱስ፡እንዲህ፡አለው፡— ሰይፍ፡የሚያነሡ፡ሁሉ፡በሰይፍ፡ይጠፋሉና፡ሰይፍህን፡ወደ፡ስፍራው፡መልስ። ፶፫ ወይስ፡አባቴን፡እንድለምን፡እርሱም፡አሁን፡ከአሥራ፡ሁለት፡ጭፍሮች፡የሚበዙ፡መላእክት፡እንዲሰድልኝ፡የማይቻል፡ይመስልሃልን? ፶፬ እንዲህ፡ከሆነስ፡— እንደዚህ፡ሊሆን፡ይገባል፡የሚሉ፡መጻሕፍት፡እንዴት፡ይፈጸማሉ? ፶፭ በዚያን፡ሰዓት፡ኢየሱስ፡ለሕዝቡ፡— ወንበዴን፡እንደምትይዙ፡ሰይፍና፡ጐመድ፡ይዛችሁ፡ልትይዙኝ፡ወጣችሁን? በመቅደስ፡ዕለት፡ዕለት፡እያስተማርሁ፡ከእናንተ፡ጋር፡ስቀመጥ፡ሳለሁ፡አልያዛችሁኝም። ፶፮ ነገር፡ግን፡ይህ፡ሁሉ፡የሆነ፡የነቢያት፡መጻሕፍት፡ይፈጸሙ፡ዘንድ፡ነው፡አለ። በዚያን፡ጊዜ፡ደቀ፡መዛሙርቱ፡ሁሉ፡ትተውት፡ሸሹ።

፶፯ ኢየሱስን፡የያዙትም፡ጻፎችና፡ሽማግሎች፡ወደ፡ተከማቹበት፡ወደ፡ሊቀ፡ካህናቱ፡ወደ፡ቀያፋ፡ወሰዱት። ፶፰ ጴጥሮስ፡ግን፡እስከ፡ሊቀ፡ካህናቱ፡ግቢ፡ድረስ፡ሩቅ፡ሆኖ፡ተከተለው፤ የነገሩንም፡ፍጻሜ፡ያይ፡ዘንድ፡ወደ፡ውስጥ፡ገብቶ፡ከሎሌዎቹ፡ጋር፡ተቀመጠ። ፶፱ የካህናት፡አለቆችና፡ሽማግሎች፡ሸንጎውም፡ሁሉ፡እንዲገድሉት፡በኢየሱስ፡ላይ፡የሐሰት፡ምስክር፡ይፈልጉ፡ነበር፤ ፷ አላገኙም፤ ብዙም፡የሐሰት፡ምስክሮች፡ምንም፡ቢቀርቡ፡አላገኙም። በኋላም፡ሁለት፡ቀርበው፡— ፷፩ ይህ፡ሰው፡— የእግዚአብሔርን፡ቤተ፡መቅደስ፡አፍርሼ፡በሦስት፡ቀን፡ልሠራው፡እችላለሁ፡ብሎአል፡አሉ። ፷፪ ሊቀ፡ካህናቱም፡ተነሥቶ፡— እነዚህ፡ለሚመሰክሩብህ፡አንድ፡ስንኳ፡አትመልስምን? አለው። ፷፫ ኢየሱስ፡ግን፡ዝም፡አለ። ሊቀ፡ካህናቱም፡— አንተ፡የእግዚአብሔር፡ልጅ፡ክርስቶስ፡የሆንህ፡እንደ፡ሆነ፡እንድትነግረን፡በሕያው፡እግዚአብሔር፡አምልሃለሁ፡አለው። ፷፬ ኢየሱስም፡— አንተ፡አልህ፤ ነገር፡ግን፡እላችኋለሁ፤ ከእንግዲህ፡ወዲህ፡የሰው፡ልጅ፡በኃይል፡ቀኝ፡ሲቀመጥ፡በሰማይም፡ደመና፡ሲመጣ፡ታያላችሁ፡አለው። ፷፭ በዚያን፡ጊዜ፡ሊቀ፡ካህናቱ፡ልብሱን፡ቀዶ፡— ተሳድቦአል፤ እንግዲህ፡ወዲህ፡ምስክሮች፡ስለ፡ምን፡ያስፈልጉናል? እነሆ፤ ስድቡን፡አሁን፡ሰምታችኋል፤ ፷፮ ምን፡ይመስላችኋል? አለ። እነርሱም፡— ሞት፡ይገባዋል፡ብለው፡መለሱ። ፷፯ በዚያን፡ጊዜ፡በፊቱ፡ተፉበት፡ጐሰሙትም፤ ሌሎችም፡በጥፊ፡መትተው፡— ፷፰ ክርስቶስ፡ሆይ፤ በጥፊ፡የመታህ፡ማን፡ነው? ትንቢት፡ተናገርልን፡አሉ።

፷፱ ጴጥሮስም፡ከቤት፡ውጭ፡በአጥሩ፡ግቢ፡ተቀምጦ፡ነበር፤ አንዲት፡ገረድም፡ወደ፡እርሱ፡ቀርባ፡— አንተ፡ደግሞ፡ከገሊላው፡ከኢየሱስ፡ጋር፡ነበርህ፡አለችው። ፸ እርሱ፡ግን፡— የምትዪውን፡አላውቀውም፡ብሎ፡በሁሉ፡ፊት፡ካደ። ፸፩ ወደ፡በሩም፡ሲወጣ፡ሌላይቱ፡አየችውና፡በዚያ፡ላሉት፡— ይህ፡ደግሞ፡ከናዝሬቱ፡ከኢየሱስ፡ጋር፡ነበረ፡አለች። ፸፪ ዳግመኛም፡ሲምል፡— ሰውየውን፡አላውቀውም፡ብሎ፡ካደ። ፸፫ ጥቂትም፡ቈይተው፡በዚያ፡ቆመው፡የነበሩ፡ቀርበው፡ጴጥሮስን፡— አነጋገርህ፡ይገልጥሃልና፡በእውነት፡አንተ፡ደግሞ፡ከእነርሱ፡ወገን፡ነህ፡አሉት። ፸፬ በዚያን፡ጊዜ፡— ሰውየውን፡አላውቀውም፡ብሎ፡ሊረግምና፡ሊምል፡ጀመረ። ወዲያውም፡ዶሮ፡ጮኸ። ፸፭ ጴጥሮስም፡— ዶሮ፡ሳይጮኽ፡ሦስት፡ጊዜ፡ትክደኛለህ፡ያለው፡የኢየሱስ፡ቃል፡ትዝ፡አለው፡ወደ፡ውጭም፡ወጥቶ፡መራራ፡ልቅሶ፡አለቀሰ።

## ምዕራፍ፡፳፯።

፩ ሲነጋም፡የካህናት፡አለቆችና፡የሕዝቡ፡ሽማግሎች፡ሁሉ፡ሊገድሉት፡በኢየሱስ፡ላይ፡ተማከሩ፤ ፪ አስረውም፡ወሰዱት፤ ለገዢው፡ለጴንጤናዊው፡ጲላጦስም፡አሳልፈው፡ሰጡት።

፫ በዚያን፡ጊዜ፡አሳልፎ፡የሰጠው፡ይሁዳ፡እንደ፡ተፈረደበት፡አይቶ፡ተጸጸተ፤ ሠላሳውንም፡ብር፡ለካህናት፡አለቆችና፡ለሽማግሎች፡መልሶ፡— ፬ ንጹሕ፡ደም፡አሳልፌ፡በመስጠቴ፡በደልሁ፡አለ። እነርሱ፡ግን፡— እኛስ፡ምን፡

፳፮። ፵፯—፶፮፤ ማር. ፲፬ ፥ ፵፫—፶፤ ሉቃ. ፳፪ ፥ ፵፯—፶፫፤ ዮሐ. ፲፰ ፥ ፫—፲፩። ፶፪፤ ዮሐ. ፲፰ ፥ ፲፩። ፶፯—፷፰፤ ማር. ፲፬ ፥ ፶፫—፷፭፤ ዮሐ. ፲፰ ፥ ፲፪፡፲፫፡፲፱—፳፬፤ ሉቃ. ፳፪ ፥ ፶፬። ፷፩፤ ዮሐ. ፪ ፥ ፲፱። ፷፬፤ ዮሐ. ፩ ፥ ፶፩። ፷፯—፷፰፤ ሉቃ. ፳፪ ፥ ፷፫—፷፭። ፷፯፤ ዘዳ. ፲፰ ፥ ፳። ፷፰፤ ዮሐ. ፲ ፥ ፴፫። ፷፯፤ ዘሌ. ፳፬ ፥ ፲፮። ፷፰፤ ኢሳ. ፶ ፥ ፮። ፷፱—፸፭፤ ማር. ፲፬ ፥ ፷፮—፸፪፤ ሉቃ. ፳፪ ፥ ፶፭—፷፪፤ ዮሐ. ፲፰ ፥ ፲፯—፳፯፤ ፳፭—፳፯።

፳፯። ፩፡፪፤ ማር. ፲፭ ፥ ፩፤ ሉቃ. ፳፫ ፥ ፩፤ ዮሐ. ፲፰ ፥ ፳፰። ፫፤ ሥራ. ፩ ፥ ፲፰፡፲፱።

፭፤ እግዶን ? አንተው፡ ተጠንቀቅ፡ አሉ ። ብሩንም፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ጥሎ ፡ ሄደና ፡ ታንቆ ፡ ሞተ ።
፮፤ የካህናት ፡ አለቆችም ፡ ብሩን ፡ አንሥተው ፡— የደም ፡ ዋጋ ፡ ነውና ፡ ወደ ፡ መባ ፡ ልንጨምረው ፡ አልተፈቀደም ፡ አሉ ። ተማክረውም ፡
፯፤ የሸክላ ሠሪውን፡መሬት፡ለእንግዶች ፡ መቃብር ፡
፰፤ ገዙበት ። ስለዚህ ፡ ያ ፡ መሬት ፡ እስከ ፡ ዛሬ፡
፱፤ ድረስ፡ የደም፡ መሬት፡ ተባለ ። በዚያን፡ ጊዜ፡ በነቢዩ ፡ በኤርምያስ ፡ የተባለው ፡—

ከእስራኤል ፡ ልጆችም ፡ አንዳንዶቹ፡ የገመቱትን ፡ የተገመተውን ፡ ዋጋ ፡ ሠላሳ ፡ ብር ፡
፲፡ ያዙ ፡ ጌታም ፡ እንዳዘዘኝ ፡ ስለ ፡ ሸክላ ፡ ሠሪ፡ መሬት ፡ሰጡት ፡

የሚል ፡ ተፈጸመ ።

፲፩፤ ኢየሱስም ፡ በገዢው ፡ ፊት ፡ ቆመ ፤ ገዢውም ፡— የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ አንተ ፡ ነህን ? ብሎ ፡ ጠየቀው ፤ ኢየሱስም ፡— አንተ ፡ አልህ፡
፲፪፤ አለው ። የካህናት ፡ አለቆችም ፡ ሽማግሌችም ፡
፲፫፤ ሲከሱት ፡ ምንም ፡ አልመለሰም ። በዚያን፡ ጊዜ፡ ጲላጦስ ፡— ስንት ፡ ያህል ፡ እንዲመሰክሩብህ ፡
፲፬፤ አትሰማምን ? አለው ። ገዢውም ፡ እጅግ ፡ እስኪደነቅ ፡ ድረስ ፡ አንዲት ፡ ቃል ፡ ስንኳ ፡ አልመለሰለትም ።

፲፭፤ በዚያም ፡ በዓል ፡ ሕዝቡ ፡ የወደዱትን ፡ አንድ፡ እስረኛ ፡ ሊፈታላቸው ፡ ለገዢው ፡ ልማድ ፡ ነበ
፲፮፤ ረው ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ በርባን ፡ የሚባል ፡
፲፯፤ በጣም ፡ የታወቀ ፡ እስረኛ ፡ ነበራቸው ። እንግዲህ ፡ እነርሱ ፡ ተሰብስበው ፡ ሳሉ ፡ ጲላጦስ ፡— በርባንን ፡ ወይስ ፡ ክርስቶስ ፡ የተባለውን ፡ ኢየሱስን ፡ ማንኛውን ፡ ልፈታላችሁ ፡ ትወዳላችሁ ?
፲፰፤ አላቸው ፤ በቅንዓት ፡ አሳልፈው ፡ እንደ ፡ ሰጡት ፡
፲፱፤ ያውቅ ፡ ነበርና ። እርሱም ፡ በፍርድ ፡ ወንበር ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፡ ሚስቱ ፡— ስለ ፡ እርሱ ፡ ዛሬ ፡ በሕልም ፡ እጅግ ፡ መከራ ፡ ተቀብያለሁና ፡ በዚያ ፡ ጻድቅ ፡ ሰው ፡ ምንም ፡ አታድርግ ፡ ብላ ፡ ላከች
፳፤ በት ። የካህናት ፡ አለቆችና ፡ ሽማግሌች ፡ ግን ፡ በርባንን ፡ እንዲለምኑ ፡ ኢየሱስን ፡ ግን ፡ እንዲያ
፳፩፤ ጠፉ ፡ ሕዝቡን ፡ አባበሉ ። ገዢውም ፡ መልሶ፡— ከሁለቱ ፡ ማንኛውን ፡ ልፈታላችሁ ፡ ትወዳላችሁ ? አላቸው ፤ እነርሱም ፡— በርባንን ፡ አሉ ።
፳፪፤ ጲላጦስ ፡— ክርስቶስ ፡ የተባለውን ፡ ኢየሱስን ፡ እንግዲህ ፡ ምን ፡ ላድርገው ? አላቸው ፤ ሁሉም ፡—
፳፫፤ ይሰቀል ፡ አሉ ። ገዢውም ፡— ምን ፡ ነው ? ያደረገው ፡ ክፉት ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለ ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡— ይሰቀል ፡ እያሉ ፡ ጩኸት ፡ አበዙ ።
፳፬፤ ጲላጦስም ፡ ሁከት ፡ እንዲጀመር ፡ እንጂ ፡ አንዳች ፡ እንዳይረባ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ውኃ ፡ አንሥቶ ፡— እኔ ፡ ከዚህ ፡ ጻድቅ ፡ ሰው ፡ ደም ፡ ንጹሕ ፡ ነኝ ፤ እናንተ ፡ ተጠንቀቁ ፡ ሲል ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ እጁን ፡ ታጠበ ።
፳፭፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ መልሰው ፡— ደሙ ፡ በእኛና ፡ በልጆቻችን ፡ ላይ ፡ ይሁን ፡ አሉ ።
፳፮፤ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በርባንን ፡ ፈታላቸው ፤ ኢየሱስን ፡ ግን ፡ ገርፎ ፡ ሊሰቀል ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠ ።

፳፯፤ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የገዢው ፡ ወታደሮች ፡ ኢየሱስን ፡ ወደ ፡ ገዢው ፡ ግቢ ፡ ውሥጥ ፡ወሰዱት ፡ ጭፍራውንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አከማቹ ።
፳፰፤ ልብሱንም ፡ ገፈው ፡ ቀይ ፡ ልብስ ፡ አለበሱት ፤
፳፱፤ ከእሾህም ፡ አክሊል ፡ጎንጉነው ፡ በራሱ ፡ ላይ ፤ በቀኝ ፡ እጁም ፡ መቃ ፡ አኖሩ ፤ በፊቱም ፡ ተንበርክከው ፡— የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ሆይ ፤ ሰላም ፡ ለአንተ ፡ ይሁን ፡ እያሉ ፡ ዘበቱበት ፤ ተፉበትም ፡
፴፤ መቃውንም ፡ ይዘው ፡ ራሱን ፡ መቱት ። ከዘበቱ
፴፩፤ በትም ፡ በኋላ ፡ቀዩን ፡ ልብስ ፡ ገፈፉት ፤ ልብሱንም ፡ አለበሱት ፡ ሊሰቅሉትም ፡ ወሰዱት ።

፴፪፤ ሲወጡም ፡ ስምዖን ፡ የተባለ ፡ የቀሬናን ፡ ሰው ፡ አገኙ ፤ እርሱንም ፡ መስቀሉን ፡ ይሸከም ፡ ዘንድ ፡
፴፫፤ አስገደዱት ። ትርጓሜው ፡ የራስ ፡ ቅል ፡ስፍራ ፡ ወደሚሆን ፡ ጎልጎታ ፡ ወደሚባለው ፡ ስፍራ ፡
፴፬፤ በደረሱ ፡ ጊዜም ፤ በሐሞት ፡ የተደባለቀ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ሊጠጣ ፡ አቀረቡለት ፤ ቀምሶም ፡
፴፭፤ ሊጠጣው ፡ አልወደደም ። ከሰቀሉትም ፡ በኋላ ፡
፴፮፤ ልብሱን ፡ ዕጣ ፡ ጥለው ፡ ተካፈሉ ፤ በዚያም ፡ ተቀ
፴፯፤ ምጠው ፡ ይጠብቁት ፡ ነበር ። ይህ ፡ ኢየሱስ ፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ ነው ፡ የሚል ፡ የክሱን ፡ጽሕፈት ፡ ከራሱ ፡ በላይ ፡ አኖሩ ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡
፴፰፤ ሁለት ፡ ወንበዶች ፡ አንዱ ፡ በቀኝ ፡ አንዱም ፡ በግራ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተሰቀሉ ። የሚያልፉ
፴፱፤ ትም ፡ ራሳቸውን ፡ እየነቀነቁ ፡ ይሰድቡት ፡ ነበ
፵፤ ርና ፡— ቤተ ፡ መቅደስን ፡ የምታፈርስ ፡ በሦስት ፡ ቀንም ፡ የምትሠራው ፡ ራስህን ፡ አድን ፤ የእግዚአብሔር ፡ ልጅስ ፡ ከሆንህ ፡ ከመስቀል ፡ ውረድ ፡
፵፩፤ አሉት ። እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ የካህናት ፡ አለቆች ፡ ከጻፎችና ፡ ከሽማግሌች ፡ ጋር ፡ እየዘበቱ
፵፪፤ በት ፡ እንዲህ ፡ አሉ ፡— ሌሎችን ፡ አዳነ ፤ ራሱን ፡ ሊያድን ፡ አይችልም ፤ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ከሆነ ፤ አሁን ፡ ከመስቀል ፡ ይውረድ ፡ እኛም ፡
፵፫፤ እናምንበታለን ። በእግዚአብሔር ፡ ታምኖአል ፤ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነኝ ፡ ብሎአልና ፡ ከወደ
፵፬፤ ደውስ ፡ አሁን ፡ ያድነው ። ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የተሰቀሉት ፡ ወንበዶች ፡ ደግሞ ፡ ያንኑ ፡ እያሉ ፡ ይነቅፉት ፡ ነበር ።

፵፭፤ ከስድስት ፡ ሰዓትም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘጠኝ ፡ ሰዓት ፡ ድረስ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ጨለማ ፡
፵፮፤ ሆነ ። በዘጠኝ ፡ ሰዓትም ፡ ኢየሱስ ፡— ኤሎሄ ፡ ኤሎሄ ፡ ላማ ፡ ሰበቅታኒ ? ብሎ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ጮኸ ። ይህም ፡— አምላኬ ፡ አምላኬ ፤ ስለ ፡ ምን ፡

፳፯። ፭፤ የሐዋ. ፩፥፲፰። ፮፤ የሐዋ. ፩፥፲፱። ፱፡ ፲፤ ዘካ. ፲፩፥፲፪። ፲፩–፲፬፤ ማር. ፲፭፥፪–፭፤ ሉቃ. ፳፫፥፪፡፫፤ ዮሐ. ፲፰፥፴፫–፴፰። ፲፩፤ ኢሳ. ፶፫፥፯። ፲፭–፳፮፤ ማር. ፲፭፥፮–፲፭፤ ሉቃ. ፳፫፥፲፫–፳፭፤ ዮሐ. ፲፰፥፴፱፤ ፲፱፥፲፮። ፳፬፤ ዘዳግ. ፳፩፥፮–፰። ፳፮፤ ኢሳ. ፶፥፮፤ ፶፫፥፭፤ ዮሐ. ፲፱፥፩። ፳፯–፴፩፤ ማር. ፲፭፥፲፮–፳፤ ዮሐ. ፲፱፥፪፡፫። ፴፤ ምሳ. ፳፯፥፳፯። ፴፬፤ ማር. ፲፭፥፳፫፤ ሉቃ. ፳፫፥፳፯። ፴፯–፵፬፤ ማር. ፲፭፥፳፬–፴፪፤ ሉቃ. ፳፫፥፴፫–፴፱፤ ዮሐ. ፲፱፥፲፰–፳፬። ፴፬፤ መዝ. ፷፱፥፳፩። ፴፭፤ መዝ. ፳፪፥፲፰። ፵፩፤ መዝ. ፳፪፥፯። ፵፫፤ ዮሐ. ፳፪፥፳፪። ፵፬፤ መዝ. ፳፪፥፰። ፵፮፤ ሉቃ. ፳፫፥፵፬–፵፱። ፵፮፤ መዝ. ፳፪፥፩።

ተውኸኝ ? ማለት ፡ ነው ። ፵፯ በዚያም ፡ ከቆሙት ፡ ሰዎች ፡ ሰምተው ፡— ይህስ ፡ ኤልያስን ፡ ይጠራል ፡ አሉ ። ፵፰ ወዲያውም ፡ ከእነርሱ ፡ አንዱ ፡ ሮጠ ፤ ሰፍነግም ፡ ይዞ ፡ ሆምጣጤ ፡ ሞላበት ፥ በመቃም ፡ አድርጎ ፡ አጠጣው ። ፵፱ ሌሎቹ ፡ ግን ፡— ተው ፥ ኤልያስ ፡ መጥቶ ፡ ያድነው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንይ ፡ አሉ ። ፶ ኢየሱስም ፡ ሁለተኛ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ጮኾ ፡ ነፍሱን ፡ ተወ ።

፶፩ እነሆም ፥ የቤተ ፡ መቅደስ ፡ መጋረጃ ፡ ከላይ ፡ እስከ ፡ ታች ፡ ከሁለት ፡ ተቀደደ ፥ ምድርም ፡ ተናወጠች ፥ ዓለቶችም ፡ ተሰነጠቁ ፤ ፶፪ መቃብሮችም ፡ ተከፈቱ ፥ ተኝተው ፡ ከነበሩትም ፡ ከቅዱሳን ፡ ብዙ ፡ ሥጋዎች ፡ ተነሡ ፤ ፶፫ ከትንሣኤውም ፡ በኋላ ፡ ከመቃብሮች ፡ ወጥተው ፡ ወደ ፡ ቅድስት ፡ ከተማ ፡ ገቡና ፡ ለብዙዎች ፡ ታዩ ። ፶፬ የመቶ ፡ አለቃም ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ኢየሱስን ፡ የሚጠብቁ ፡ መናወጡንና ፡ የሆነውን ፡ ነገር ፡ አይተው ፡— ይህ ፡ በእውነት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፡ ብለው ፡ እጅግ ፡ ፈሩ ።

፶፭ ኢየሱስን ፡ እያገለገሉ ፡ ከገሊላ ፡ የተከተሉት ፡ ብዙ ፡ ሴቶች ፡ በሩቅ ፡ ሆነው ፡ ሲመለከቱ ፡ በዚያ ፡ ነበሩ ፤ ፶፮ ከእነርሱም ፡ መግደላዊት ፡ ማርያምና ፡ የያዕቆብና ፡ የዮሳ ፡ እናት ፡ ማርያም ፡ የዘብዴዎስም ፡ የልጆቹ ፡ እናት ፡ ነበሩ ።

፶፯ በመሸም ፡ ጊዜ ፡ ዮሴፍ ፡ የተባለው ፡ ባለ ፡ ጠጋ ፡ ሰው ፡ ከአርማትያስ ፡ መጣ ፥ እርሱም ፡ ደግሞ ፡ የኢየሱስ ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ነበረ ፤ ፶፰ ይኸውም ፡ ወደ ፡ ጲላጦስ ፡ ቀርቦ ፡ የኢየሱስን ፡ ሥጋ ፡ ለመነ ። ጲላጦስም ፡ እንዲሰጡት ፡ አዘዘ ። ፶፱ ዮሴፍም ፡ ሥጋውን ፡ ይዞ ፡ በንጹሕ ፡ በፍታ ፡ ከፈነው ፥ ፷ ከዓለት ፡ በወቀረው ፡ በአዲሱ ፡ መቃብርም ፡ አኖረው ፥ በመቃብሩም ፡ ደጃፍ ፡ ታላቅ ፡ ድንጋይ ፡ አንከባሎ ፡ ሄደ ። ፷፩ መግደላዊት ፡ ማርያምም ፡ ሁለተኛይቱም ፡ ማርያም ፡ በመቃብሩ ፡ አንጻር ፡ ተቀምጠው ፡ በዚያ ፡ ነበሩ ።

፷፪ በማግሥቱም ፡ ከመዘጋጀት ፡ በኋላ ፡ በሚሆነው ፡ ቀን ፥ የካህናት ፡ አለቆችና ፡ ፈሪሳውያን ፡ ወደ ፡ ጲላጦስ ፡ ተሰብስበው ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ፷፫ ያ ፡ አሳች ፡ በሕይወቱ ፡ ገና ፡ ሳለ ፡— ከሦስት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ እነሣለሁ ፡ እንዳለ ፡ ትዝ ፡ አለን ። ፷፬ እንግዲህ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ መጥተው ፡ በሌሊት ፡ እንዳይሰርቁት ፡ ለሕዝቡም ፡— ከሙታን ፡ ተነሣ ፡ እንዳይሉ ፥ የኋለኛይቱ ፡ ስሕተት ፡ ከፊተኛይቱ ፡ ይልቅ ፡ የከፋች ፡ ትሆናለችና ፡ መቃብሩ ፡ እስከ ፡ ሦስተኛ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ እንዲጠበቅ ፡ እዘዝ ፡ አሉት ። ፷፭ ጲላጦስም ፡— ጠባቆች ፡ አሉአችሁ ፤ ሂዱና ፡ እንዳወቃችሁ ፡ አስጠብቁ ፡ አላቸው ። ፷፮ እነርሱም ፡ ሄደው ፡ ከጠባቆች ፡ ጋር ፡ ድንጋዩን ፡ አትመው ፡ መቃብሩን ፡ አስጠበቁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

፩ በሰንበትም ፡ መጨረሻ ፡ መጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ሲነጋ ፡ መግደላዊት ፡ ማርያምና ፡ ሁለተኛይቱ ፡ ማርያም ፡ መቃብሩን ፡ ሊያዩ ፡ መጡ ። ፪ እነሆም ፥ የጌታ ፡ መልአክ ፡ ከሰማይ ፡ ስለ ፡ ወረደ ፡ ታላቅ ፡ የምድር ፡ መናወጥ ፡ ሆነ ፤ ቀርቦም ፡ ድንጋዩን ፡ አንከባሎ ፡ በላዩ ፡ ተቀመጠ ። ፫ መልኩም ፡ እንደ ፡ መብረቅ ፡ ልብሱም ፡ እንደ ፡ በረዶ ፡ ነጭ ፡ ነበረ ። ፬ ጠባቆቹም ፡ እርሱን ፡ ከመፍራት ፡ የተነሣ ፡ ተናወጡ ፡ እንደ ፡ ሞቱም ፡ ሆኑ ። ፭ መልአኩም ፡ መልሶ ፡ ሴቶቹን ፡ አላቸው ፡— እናንተስ ፡ አትፍሩ ፤ የተሰቀለውን ፡ ኢየሱስን ፡ እንድትሹ ፡ አውቃለሁና ፤ ፮ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ተነሥቶአልና ፡ በዚህ ፡ የለም ፤ የተኛበትን ፡ ስፍራ ፡ ኑና ፡ እዩ ። ፯ ፈጥናችሁም ፡ ሂዱና ፡— ከሙታን ፡ ተነሣ ፥ እነሆም ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ ይቀድማችኋል ፡ በዚያም ፡ ታዩታላችሁ ፡ ብላችሁ ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ንገሩአቸው ። እነሆ ፥ ነገርኋችሁ ። ፰ በፍርሃትና ፡ በታላቅ ፡ ደስታም ፡ ፈጥነው ፡ ከመቃብር ፡ ሄዱ ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ሊያወሩ ፡ ሮጡ ። ፱ እነሆም ፥ ኢየሱስ ፡ አገኛቸውና ፡— ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡ ቀርበው ፡ እግሩን ፡ ይዘው ፡ሰገዱለት ። ፲ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ኢየሱስ ፡— አትፍሩ ፤ ሄዳችሁ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ እንዲሄዱ ፡ ለወንድሞቼ ፡ተናገሩ ፥ በዚያም ፡ ያዩኛል ፡ አላቸው ።

፲፩ ሲሄዱም ፡ሳሉ ፡ እነሆ ፥ ከጠባቆቹ ፡ አንዳንድ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ መጥተው ፡ የሆነውን ፡ ሁሉ ፡ ለካህናት ፡ አለቆች ፡ አወሩ ። ፲፪ ከሽማግሌዎች ፡ ጋርም ፡ ተሰብስበው ፡ ተማክሩና ፡ ለጭፍሮች ፡ ብዙ ፡ ገንዘብ ፡ ሰጥተው ፡— ፲፫ እኛ ፡ ተኝተን ፡ ሳለን ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ በሌሊት ፡ መጥተው ፡ሰረቁት ፡ በሉ ። ፲፬ ይህም ፡ በገዢው ፡ ዘንድ ፡ የተሰማ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ እኛ ፡ እናስረዳዋለን ፡ እናንተም ፡ ያለ ፡ሥጋት ፡ እንድትሆኑ ፡ እናደርጋለን ፡ አሉአቸው ። ፲፭ እነርሱም ፡ ገንዘቡን ፡ ተቀብለው ፡ እንደ ፡ አስተማሩአቸው ፡ አደረጉ ። ይህም ፡ ነገር ፡ በአይሁድ ፡ ዘንድ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ሲወራ ፡ ይኖራል ።

፲፮ አሥራ ፡ አንዱ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ግን ፡ ኢየሱስ ፡ ወዳዘዛቸው ፡ ተራራ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ ሄዱ ፥ ፲፯ ባዩትም ፡ ጊዜ ፡ ሰገዱለት ፤ የተጠራጠሩ ፡ ግን ፡ ነበሩ ። ፲፰ ኢየሱስም ፡ ቀረበና ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገራቸው ፡— ሥልጣን ፡ ሁሉ ፡ በሰማይና ፡ በምድር ፡ ተሰጠኝ ። ፲፱ እንግዲህ ፡ ሂዱና ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ በአብ ፡ በወልድና ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ስም ፡ እያጠመቃችኋቸው ፡ ፳ ያዘዝኋችሁንም ፡ ሁሉ ፡ እንዲጠብቁ ፡ እያስተማራችኋቸው ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ አድርጓቸው ። እነሆም ፡ እኔ ፡ እስከ ፡ ዓለም ፡ ፍጻሜ ፡ ድረስ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ነኝ ።

፳፯ ፤ ... ማቴ. ፳፮ ፥ ፳፬ ። ፶፮ ፤ ዘካ. ፳፩ ፥ ... ። ፶፭—፶፮ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፵፩—፵፯ ፤ ሉቃ. ፳፫ ፥ ፵፱ ። ፶፱ ፤ ምሳ. ... ። ... ሉቃ. ... ። ... ማር. ፲፭ ፥ ፵፪—፵፯ ፤ ሉቃ. ... ዮሐ. ፲፱ ፥ ፴፰—፵፪ ፤ ኢሳ. ፶፫ ፥ ፱ ። ... ምሳ. ... ።

፳፰ ። ፩—፰ ፤ ማር. ፲፮ ፥ ፩—፰ ፤ ሉቃ. ፳፬ ፥ ፩—፲ ፤ ዮሐ. ፳ ፥ ፩ ። ... ። ... ። [illegible]

# የጌታችን፡የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ወንጌል፡
# ቅዱስ፡ማርቆስ፡እንደ፡ጻፈው።

## ምዕራፍ፡፩።

፩፤ የእግዚአብሔር፡ልጅ፡የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ወንጌል፡መጀመሪያ።

፪፡፫፤ እነሆ፥ መንገድህን፡የሚጠርግ፡መልክተኛዬን፡በፊትህ፡እልካለሁ፡የጌታን፡መንገድ፡አዘጋጁ፡ጥርጊያውንም፡አቅኑ፡እያለ፡በምድረ፡በዳ፡የሚጮኽ፡ሰው፡ድምፅ፡

ተብሎ፡በነቢዩ፡በኢሳይያስ፡እንደ፡ተጻፈ፥ ፬፤ ዮሐንስ፡በምድረ፡በዳ፡እያጠመቀ፡የንስሐንም፡ጥምቀት፡ለኃጢአት፡ስርየት፡እየሰበከ፡መጣ። ፭፤ የይሁዳም፡አገር፡ሁሉ፡የኢየሩሳሌምም፡ሰዎች፡ሁሉ፡ወደ፡እርሱ፡ይወጡ፡ነበር፥ኃጢአታቸውንም፡እየተናዘዙ፡በዮርዳኖስ፡ወንዝ፡ከእርሱ፡ይጠመቁ፡ነበር። ፮፤ ዮሐንስም፡የግመል፡ጠጉር፡ለብሶ፡በወገቡ፡ጠፍር፡ይታጠቅ፡አንበጣና፡የበረሀ፡ማርም፡ይበላ፡ነበር። ፯፤ ተጐንብሼ፡የጫማውን፡ጠፍር፡መፍታት፡የማይገባኝ፡ከእኔ፡የሚበረታ፡በኋላዬ፡ ፰፤ ይመጣል። እኔ፡በውኃ፡አጠመቅኋችሁ፡እርሱ፡ግን፡በመንፈስ፡ቅዱስ፡ያጠምቃችኋል፡እያለ፡ይሰብክ፡ነበር።

፱፤ በዚያ፡ወራትም፡ኢየሱስ፡ከገሊላ፡ናዝሬት፡መጥቶ፡ከዮሐንስ፡በዮርዳኖስ፡ወንዝ፡ተጠ ፲፤ መቀ። ወዲያውም፡ከውኃው፡በወጣ፡ጊዜ፡ሰማያት፡ሲቀደዱ፡መንፈስም፡እንደ፡ርግብ፡ ፲፩፤ ሲወርድበት፡አየና፡—የምወድህ፡ልጄ፡አንተ፡ነህ፥በአንተ፡ደስ፡ይለኛል፡የሚል፡ድምፅ፡ከሰማያት፡መጣ።

፲፪፤ ወዲያውም፡መንፈስ፡ወደ፡ምድረ፡በዳ፡ ፲፫፤ አወጣው። በምድረ፡በዳም፡ከሰይጣን፡እየተፈተነ፡አርባ፡ቀን፡ሰነበተ፤ከአራዊትም፡ጋር፡ነበረ፥መላእክቱም፡አገለገሉት።

፲፬፡፲፭፤ ዮሐንስም፡አልፎ፡ከተሰጠ፡በኋላ፡ኢየሱስ፡የእግዚአብሔርን፡መንግሥት፡ወንጌል፡እየሰበከና፡—ዘመኑ፡ተፈጸመ፡የእግዚአብሔርም፡መንግሥት፡ቀርባለች፤ ንስሐ፡ግቡ፡በወንጌልም፡እመኑ፡እያለ፡ወደ፡ገሊላ፡መጣ።

፲፮፤ በገሊላ፡ባሕርም፡አጠገብ፡ሲያልፍ፡ስምዖንን፡ወንድሙንም፡እንድርያስን፡መረባቸውን፡ወደ፡ባሕር፡ሲጥሉ፡አየ፥ ዓሣ፡አጥማጆች፡ ፲፯፤ ነበሩና። ኢየሱስም፡—በኋላዬ፡ኑና፡ሰዎችን፡አጥማጆች፡እንድትሆኑ፡አደርጋችኋለሁ፡አላ ፲፰፤ ቸው። ወዲያውም፡መረባቸውን፡ትተው፡ ፲፱፤ ተከተሉት። ከዚያም፡ጥቂት፡እልፍ፡ብሎ፡የዘብዴዎስን፡ልጅ፡ያዕቆብን፡ወንድሙንም፡ዮሐንስን፡ደግሞ፡በታንኳ፡ላይ፡መረባቸውን፡ ፳፤ ሲያበጁ፡አየ። ወዲያውም፡ጠራቸው፡አባታቸውንም፡ዘብዴዎስን፡ከሞያተኞቹ፡ጋር፡በታንኳ፡ላይ፡ትተው፡ተከትለውት፡ሄዱ።

፳፩፤ ወደ፡ቅፍርናሆምም፡ገቡ፤ወዲያውም፡በሰንበት፡ወደ፡ምኵራብ፡ገብቶ፡አስተማረ። ፳፪፤ እንደ፡ባለ፡ሥልጣን፡ያስተምራቸው፡ነበር፡እንጂ፡እንደ፡ጻፎች፡አይደለምና፡በትምህርቱ፡ተገረሙ። ፳፫፤ በዚያን፡ጊዜም፡በምኵራባቸው፡ርኵስ፡መንፈስ፡ያለው፡ሰው፡ነበረ፤ ፳፬፤ እርሱም፡—የናዝሬቱ፡ኢየሱስ፡ሆይ፥ከአንተ፡ጋር፡ምን፡አለን? ልታጠፋን፡መጣህን? ማን፡እንደ፡ሆንህ፡አውቄአለሁ፥የእግዚአብሔር፡ ፳፭፤ ቅዱሱ፡ብሎ፡ጮኸ። ኢየሱስም፡—ዝም፡በል፡ ፳፮፤ ከእርሱም፡ውጣ፡ብሎ፡ገሠጸው። ርኵሱም፡መንፈስ፡አንፈራገጠውና፡በታላቅ፡ድምፅ፡ ፳፯፤ ጮኾ፡ከእርሱ፡ወጣ። ሁሉም፡—ይህ፡ምንድር፡ነው? በሥልጣን፡ርኵሳን፡መናፍስትን፡ያዝዛል፡እነርሱም፡ይታዘዙለታልና፡ይህ፡አዲስ፡ትምህርት፡ምንድር፡ነው? ብለው፡ ፳፰፤ እስኪጠያየቁ፡ድረስ፡አደነቁ። ዝናውም፡ወዲያው፡በየስፍራው፡ወደ፡ገሊላ፡ዙሪያ፡ሁሉ፡ወጣ።

፳፱፤ ወዲያውም፡ከምኵራብ፡ወጥቶ፡ከያዕቆብና፡ከዮሐንስ፡ጋር፡ወደ፡ስምዖንና፡ወደ፡እንድር ፴፤ ያስ፡ቤት፡ገባ። የስምዖንም፡አማት፡በንዳድ፡ታማ፡ተኝታ፡ነበር፥ስለ፡እርስዋም፡ወዲያው፡ ፴፩፤ ነገሩት። ቀርቦም፡እጅዋን፡ይዞ፡አስነሣት፤ንዳዱም፡ወዲያው፡ለቀቃትና፡አገለገለቻቸው።

፴፪፤ ፀሐይም፡ገብቶ፡በመሸ፡ጊዜ፥የታመሙትንና፡አጋንንት፡ያደረባቸውን፡ሁሉ፡ወደ፡ ፴፫፤ እርሱ፡አመጡ፤ከተማይቱም፡ሁላ፡በደጅ፡ ፴፬፤ ተሰብስባ፡ነበር። በልዩ፡ልዩ፡ደዌም፡የታመሙትን፡ብዙዎችን፡ፈወሰ፥ብዙዎችንም፡አጋንንት፡አወጣ፥አጋንንትም፡ክርስቶስ፡መሆኑን፡አውቀው፡ነበርና፡ሲናገሩ፡አልፈቀደላቸውም።

፴፭፤ ማለዳም፡ተነሥቶ፡ገና፡ሌሊት፡ሳለ፡ወጣ፡

፩። ፪—፰፤ ማቴ. ፫፥፩—፲፩፤ ሉቃ. ፫፥፪—፲፯። ፪፤ ሚል. ፫፥፩፤ ማቴ. ፲፩፥፲። ፫፤ ኢሳ. ፵፥፫። ፮፤ ዮሐ. ፩፥፳፯። ፰፤ ዮሐ. ፩፥፴፫። ፱—፲፩፤ ማቴ. ፫፥፲፫—፲፯፤ ሉቃ. ፫፥፳፩፡፳፪፤ ዮሐ. ፩፥፴፪፡፴፬። ፲፩፤ ምዕ. ፱፥፯፤ ዮሐ. ፲፪፥፳፰፤ መዝ. ፪፥፯። ፲፪፡፲፫፤ ማቴ. ፬፥፩—፲፩፤ ሉቃ. ፬፥፩—፲፫። ፲፬፤ ማቴ. ፬፥፲፪። ፲፮—፳፤ ማቴ. ፬፥፲፰—፳፪፤ ሉቃ. ፭፥፪—፲፩። ፳፩—፳፰፤ ሉቃ. ፬፥፴፩—፴፯። ፳፪፤ ማቴ. ፯፥፳፰፡፳፱። ፳፬፤ ምዕ. ፫፥፲፩። ፳፱—፴፬፤ ማቴ. ፰፥፲፬—፲፯፤ ሉቃ. ፬፥፴፰—፵፩። ፴፬፤ ማቴ. ፰፥፬። ፴፭—፴፰፤ ሉቃ. ፬፥፵፪—፵፬። ፴፰፤ ማቴ. ፲፬፥፳፫፤ ሉቃ. ፭፥፲፮።

፴፮ ወደ፡ምድረ፡በዳም፡ሄዶ፡በዚያ፡ጸለየ ። ስም
ዖንና፡ከእርሱ፡ጋር፡የነበሩትም፡ገሥግሠው፡
፴፯ ተከተሉት፤ ባገኙትም፡ጊዜ፡— ሁሉ፡ይፈልጉ
፴፰ ሃል፡አሉት ። እርሱም፡— በዚያ፡ደግሞ፡ልሰ
ብክ፡ወደ፡ሌላ፡ስፍራ፡በቅርብ፡ወዳሉ፡መን
ደሮች፡እንሂድ፡ስለዚህ፡ወጥቻለሁና፡አላ
፴፱ ቸው ። በምኵራባቸውም፡እየሰበከ፡አጋንንት
ንም፡እያወጣ፡ወደ፡ገሊላ፡ሁሉ፡መጣ ።

፵ ለምጻምም፡ወደ፡እርሱ፡መጥቶ፡ተንበረከ
ከና፡— ብትወድስ፡ልታነጻኝ፡ትችላለህ፡ብሎ፡
፵፩ ለመነው ። ኢየሱስም፡አዘነለት፡እጁንም፡ዘር
ግቶ፡ዳሰሰውና፡— እወድዳለሁ፡ንጻ፡አለው ።
፵፪ ይህንም፡ሲናገር፡ጊዜ፡ለምጹ፡ወዲያው፡ለቀቀ
፵፫ ውና፡ነጻ ። በብርቱም፡ተናግሮ፡ወዲያው፡
፵፬ አወጣው፤ ለማንም፡አንዳች፡እንዳትናገር፡ተጠ
ንቀቅ ፥ ነገር፡ግን፡ሄደህ፡ራስህን፡ለካህን፡
አሳይ፡ለእነርሱም፡ምስክር፡እንዲሆን፡ስለ፡
መንጻትህ፡ሙሴ፡ያዘዘውን፡አቅርብ፡አለው ።
፵፭ እርሱ፡ግን፡ሲወጣ፡ብዙ፡ሊሰብክና፡ነገሩን፡
ሊያወራ፡ጀመረ ፥ ስለዚህም፡ኢየሱስ፡ተገ
ልጦ፡ወደ፡ከተማ፡መግባት፡ወደ፡ፊት፡ተሳ
ነው ፥ ነገር፡ግን፡በውጭ፡በምድረ፡በዳ፡ይኖር፡
ነበር፤ ከየስፍራውም፡ወደ፡እርሱ፡ይመጡ፡
ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ከጥቂት፡ቀን፡በኋላ፡ወደ፡ቅፍርናሆም፡
ደግሞ፡ገብቶ፡በቤት፡እንደ፡ሆነ፡ተሰማ ።
፪ በደጅ፡ያለው፡ስፍራም፡እስኪጠባቸው፡ድረስ፡
ብዙ፡ሰዎች፡ተሰበሰቡ፤ ቃሉንም፡ይነግራ
፫ ቸው፡ነበር ። አራት፡ሰዎችም፡የተሸከሙትን፡
፬ ሽባ፡አመጡለት ። ስለ፡ሕዝቡም፡ብዛት፡ወደ፡
እርሱ፡ማቅረብ፡ቢያቅታቸው፡እርሱ፡ያለበ
ትን፡የቤቱን፡ጣራ፡አነሡ ፥ ነድለውም፡ሽባው፡
፭ የተኛበትን፡አልጋ፡አወረዱ ። ኢየሱስም፡እም
ነታቸውን፡አይቶ፡ሽባውን፡— አንተ፡ልጅ ፥
፮ ኃጢአትህ፡ተሰረየችልህ፡አለው ። ከጻፎችም፡
አንዳንዶቹ፡በዚያ፡ተቀምጠው፡ነበር፡በልባ
፯ ቸውም፡— ይህ፡ሰው፡ስለ፡ምን፡እንደዚህ፡
ያለ፡ስድብ፡ይናገራል ? ከአንዱ፡ከእግዚአብ
ሔር፡በቀር፡ኃጢአት፡ሊያስተሰርይ፡ማን፡
፰ ይችላል ? ብለው፡አሰቡ ። ወዲያውም፡ኢየ
ሱስ፡በልባቸው፡እንዲህ፡እንዳሰቡ፡በመንፈሱ፡
አውቆ፡እንዲህ፡አላቸው፡— በልባችሁ፡ይህን፡
፱ ስለ፡ምን፡ታስባላችሁ ? ሽባውን፡— ኃጢአትህ፡
ተሰረየችልህ፡ከማለት፡ወይስ፡— ተነሣ፡አል
ጋህንም፡ተሸክመህ፡ሂድ፡ከማለት፡ማናቸው፡
፲ ይቀላል ? ነገር፡ግን፡ለሰው፡ልጅ፡በምድር፡
ላይ፡ኃጢአትን፡ሊያስተሰርይ፡ሥልጣን፡እን
፲፩ ዳለው፡እንድታውቁ፤ ሽባውን፡— አንተን፡እል
ሃለሁ ፥ ተነሣ ፥ አልጋህን፡ተሸክመህ፡ወደ፡
፲፪ ቤትህ፡ሂድ፡አለው ። ተነሥቶም፡ወዲያው፡
አልጋውን፡ተሸክሞ፡በሁሉ፡ፊት፡ወጣ ፥
ስለዚህም፡ሰዎች፡ሁሉ፡ተገረሙና፡— እንዲህ፡
ያለ፡ከቶ፡አላየንም፡ብለው፡እግዚአብሔርን፡
አከበሩ ።

፲፫ ደግሞም፡በባሕር፡አጠገብ፡ወጣ፤ ሕዝቡም፡
ሁሉ፡ወደ፡እርሱ፡መጡና፡አስተማራቸው ።
፲፬ ሲያልፍም፡በመቅረጫው፡ተቀምጦ፡የነበረ
ውን፡የእልፍዮስን፡ልጅ፡ሌዊን፡አየና፡—
ተከተለኝ፡አለው ። ተነሥቶም፡ተከተለው ።

፲፭ በቤቱም፡በማዕድ፡ተቀምጦ፡ሳለ ፥ ብዙ፡
ቀራጮችና፡ኃጢአተኞች፡ከኢየሱስና፡ከደቀ፡
መዛሙርቱ፡ጋር፡ተቀመጡ፤ ብዙ፡ነበሩ፡ይከ
፲፮ ተሉትም፡ነበር ። ጻፎችና፡ፈሪሳውያንም፡ከቀ
ራጮችና፡ከኃጢአተኞች፡ጋር፡ሲበላ፡አይ
ተው፡ለደቀ፡መዛሙርቱ፡— ከቀራጮችና፡
ከኃጢአተኞች፡ጋር፡የሚበላና፡የሚጠጣ፡ስለ፡
፲፯ ምንድር፡ነው ? አሉ ። ኢየሱስም፡ሰምቶ፡—
ሕመምተኞች፡እንጂ፡ብርቱዎች፡ባለ፡መድ
ኃኒት፡አያስፈልጋቸውም ፤ ኃጢአተኞችን፡
እንጂ፡ጻድቃንን፡ልጠራ፡አልመጣሁም፡አላ
ቸው ።

፲፰ የዮሐንስ፡ደቀ፡መዛሙርትና፡ፈሪሳውያን፡
ይጦሙ፡ነበር ። መጥተውም፡— የዮሐንስና፡
የፈሪሳውያን፡ደቀ፡መዛሙርት፡የሚጦሙት፡
የአንተ፡ደቀ፡መዛሙርት፡ግን፡የማይጦሙት፡
፲፱ ስለ፡ምንድር፡ነው ? አሉት ። ኢየሱስም፡አላ
ቸው፡— ሙሽራው፡ከእነርሱ፡ጋር፡ሳለ፡ሚዜ
ዎች፡ሊጦሙ፡ይችላሉን ? ሙሽራው፡ከእነ
፳ ርሱ፡ጋር፡ሳለ፡ሊጦሙ፡አይችሉም ። ነገር፡ግን፡
ሙሽራው፡ከእነርሱ፡የሚወሰድበት፡ወራት፡
፳፩ ይመጣል ፥ በዚያ፡ወራትም፡ይጦማሉ ። በአ
ረጀ፡ልብስ፡አዲስ፡እራፊ፡የሚጥፍ፡የለም፤
ቢያደርግ፡ግን ፥ አዲሱ፡መጣፊያ፡አሮጌውን፡
ይቦጭቀዋል ፥ መቀደዱም፡የባሰ፡ይሆናል ።
፳፪ በአረጀ፡አቁማዳም፡አዲስ፡የወይን፡ጠጅ፡
የሚያኖር፡የለም፡ቢያደርግ፡ግን ፥ የወይን፡
ጠጁ፡አቁማዳውን፡ያፈነዳል፡የወይኑም፡ጠጅ፡
ይፈሳል፡አቁማዳውም፡ይጠፋል፡አዲሱን፡የወ
ይን፡ጠጅ፡ግን፡በአዲስ፡አቁማዳ፡ያኖራሉ ።

፳፫ በሰንበትም፡በእርሻ፡መካከል፡ሲያልፍ፡ደቀ፡
መዛሙርቱ፡እየሄዱ፡እሸት፡ይቀጥፉ፡ጀመር ።
፳፬ ፈሪሳውያንም፡— እነሆ ፥ በሰንበት፡ያልተፈቀ
፳፭ ደውን፡ስለ፡ምን፡ያደርጋሉ ? አሉት ። እር
ሱም፡— ዳዊት፡ባስፈለገውና፡በተራበ፡ጊዜ ፥
እርሱ፡አብረውት፡ከነበሩት፡ጋር፡ያደረገውን ፥
፳፮ አብያታር፡ሊቀ፡ካህናት፡በነበረ፡ጊዜ፡ወደ፡
እግዚአብሔር፡ቤት፡እንደ፡ገባ ፥ ከካህናት፡
በቀር፡መብላት፡ያልተፈቀደውን፡የመሥዋዕ

፩። ፴–፴፰፤ ማቴ. ፰ ፥ ፪–፬ ፤ ሉቃ. ፭ ፥ ፲፪–፲፬ ። ፴፰ ፤ ዘሌዋ. ፲፬ ፥ ፪–፴፪ ።

፪። ፫–፲፪፤ ማቴ. ፱ ፥ ፪–፰ ፤ ሉቃ. ፭ ፥ ፲፰–፳፮ ። ፭ ፤ ዮሐ. ፲ ፥ ፴፫ ። ፯ ፤ ኢሳ. ፵፫ ፥ ፳፭ ። ፲፬ ፤ ዮሐ. ፭ ፥ ፳፬ ። ፲፬–፳፪ ፤ ማቴ. ፱ ፥ ፱–፲፯ ፤ ሉቃ. ፭ ፥ ፳፯–፴፰ ። ፳፫–፳፰ ፤ ዘዳግ. ፳፫ ፥ ፳፭ ፤ ማቴ. ፲፪ ፥ ፩–፰ ፤ ሉቃ. ፮ ፥ ፩–፭ ። ፳፭ ፤ ፩ ሳሙ. ፳፩ ፥ ፩–፮ ። ፳፮ ፤ ፩ ሳሙ. ፳፪ ፥ ፳ ፤ ፩ ዜና ፳፬ ፥ ፮ ፤ ዘሌዋ. ፳፬ ፥ ፭–፱ ።

ትን ፡ እንጀራ ፡ እንደ ፡ በላ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ለነበ
ሩት ፡ እንደ ፡ ሰጣቸው ፡ ከቶ ፡ አላነበባችሁምን ?
፳፯ አላቸው ። ደግሞ ፦ ሰንበት ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ተፈጥ
ሮአል ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ ሰንበት ፡ አልተፈጠ
፳፰ ረም ፤ እንዲሁም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ለሰንበት ፡ እንኳ ፡
ጌታዋ ፡ ነው ፡ አላቸው ።

ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ደግሞም ፡ ወደ ፡ ምኵራብ ፡ ገባ ፥ በዚያም ፡
፪ እጁ ፡ የሰለለች ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ሊከሱትም ፥ በሰ
ንበት ፡ ይፈውሰው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይጠባበቁት ፡
፫ ነበር ። እጁ ፡ የሰለለችውንም ፡ ሰው ፦ ተነሥ
፬ ተሀ ፡ ወደ ፡ መካከል ፡ ና ፡ አለው ። በሰንበት ፡ በጎ ፡
ማድረግ ፡ ተፈቅዶአልን ፡ ወይስ ፡ ክፉ ? ነፍስ ፡
ማዳንን ፡ ወይስ ፡ መግደል ? አላቸው ፤ እነርሱም ፡
፭ ዝም ፡ አሉ ። ስለ ፡ ልባቸውም ፡ድንዛዜ ፡ አዝኖ ፡
ዙሪያውን ፡ እየተመለከተ ፡ በቍጣ ፡ እያቸው ፥
ሰውየውንም ፦ እጅህን ፡ዘርጋ ፡ አለው ። ዘረ
፮ ጋትም ፤ እጁም ፡ዳነች ። ፈሪሳውያንም ፡ ወጥ
ተው ፡ወዲያው ፡ እንዴት ፡ አድርገው ፡ እንዲያ
ጠፉት ፡ ከሄሮድስ ፡ወገን ፡ ጋር ፡ ተማከሩበት ።
፯ ኢየሱስም ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡
ባሕር ፡ ፈቀቅ ፡ አለ ፤ ከገሊላ ፡ የመጡም ፡ ብዙ ፡
፰ ሰዎች ፡ ተከተሉት ፤ እንዴት ፡ ትልቅ ፡ ነገርም ፡
እንዳደረገው ፡ ሰምተው ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ከይ
ሁዳ ፡ ከኢየሩሳሌምም ፡ ከኤዶምያስም ፡ ከዮርዳ
ኖስ ፡ ማዶም ፡ ከጢሮስና ፡ ከሲዶና ፡ ምድርም ፡
፱ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጡ ። ሰዎቹም ፡ እንዳያጋፉት ፡
ታንኳን ፡ ያቆዩለት ፡ ዘንድ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡
፲ አዘዛቸው ፤ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ አድኖ ፡ ነበርና ፥
ስለዚህም ፡ ሥቃይ ፡ ያለባቸው ፡ ሁሉ ፡ እንዲዳ
፲፩ ስሱት ፡ ይወድቁበት ፡ ነበር ። ርኵሳን ፡ መናፍስ
ትም ፡ በዩት ፡ ጊዜ ፡ በፊቱ ፡ ተደፍተው ፦
አንተ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነህ ፡ እያሉ ፡
፲፪ ጮኹ ። እንዳይገልጡትም ፡ በጣም ፡ አዘዛቸው ።
፲፫ ወደ ፡ ተራራም ፡ ወጣ ፥ ራሱም ፡ የወደዳቸ
ውን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ጠራ ፥ ወደ ፡ እርሱም ፡ ሄዱ ።
፲፬ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ እንዲኖሩና ፡ ሊሰብክ ፡ እን
፲፭ ዲልካቸው ፥ ድውዮችንም ፡ ሊፈውሱ ፡ አጋን
ንትንም ፡ ሊያወጡ ፡ ሥልጣን ፡ ይሆንላቸው ፡
፲፮ ዘንድ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ አደረገ ፤ ስምዖንንም ፡
፲፯ ጴጥሮስ ፡ብሎ ፡ሰየመው ፤ የዘብዴዎስንም ፡ ልጅ ፡
ያዕቆብን ፡ የያዕቆብንም ፡ ወንድም ፡ ዮሐንስን ፡
ቦአኔርጌስ ፡ ብሎ ፡ ሰየማቸው ፥ የነጐድጓድ ፡
፲፰ ልጆች ፡ ማለት ፡ ነው ፤ እንድርያስንም ፡ ፊልጶስ
ንም ፡ በርተሎሜዎስንም ፡ ማቴዎስንም ፡ ቶማስ
ንም ፡ የእልፍዮስን ፡ ልጅ ፡ ያዕቆብንም ፡ ታዴዎስ
ንም ፡ ቀነናዊውንም ፡ ስምዖንን ፥ አሳልፎ ፡ የሰ ፲፱
ጠውንም ፡ የአስቆሮቱን ፡ ይሁዳን ።
፳ ወደ ፡ ቤትም ፡ መጡ ፤ እንጀራም ፡ መብላት ፡
ስንኳ ፡ እስኪሳናቸው ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ብዙ ፡
፳፩ ሰዎች ፡ ተሰበሰቡ ። ዘመዶቹም ፡ ሰምተው ፦
፳፪ አበደ ፡ ብለዋልና ፡ ሊይዙት ፡ ወጡ ። ከኢየሩሳ
ሌም ፡ የወረዱ ፡ ጻፎችም ፦ ብዔል ፡ ዜቡል ፡
አለበት ፤ ደግሞ ፦ በአጋንንት ፡ አለቃ ፡ አጋንን
፳፫ ትን ፡ ያወጣል ፡ ብለው ፡ ተናገሩ ። እነርሱንም ፡
ወደ ፡ እርሱ ፡ጠርቶ ፡ በምሳሌ ፡ አላቸው ፦ ሰይ
ጣን ፡ ሰይጣንን ፡ ሊያወጣው ፡ እንዴት ፡ ይች
፳፬ ላል ? መንግሥትም ፡ እርስ ፡ በርስዋ ፡ ከተለያ
የች ፡ ያች ፡ መንግሥት ፡ ልትቆም ፡ አትችልም ፤
፳፭ ቤትም ፡ እርስ ፡ በርሱ ፡ ከተለያየ ፡ ያ ፡ ቤት ፡
፳፮ ሊቆም ፡ አይችልም ። ሰይጣንም ፡ራሱን ፡ ተቃ
ውሞ ፡ ከተለያየ ፥ መጨረሻ ፡ ይሆንበታል ፡ እንጂ ፡
፳፯ ሊቆም ፡ አይችልም ። ነገር ፡ ግን ፡ አስቀድሞ ፡
ኃይለኛውን ፡ ሳያስር ፡ ወደ ፡ ኃይለኛው ፡ ቤት ፡
ገብቶ ፡ዕቃውን ፡ ሊበዘብዝ ፡ የሚችል ፡ የለም ፥
ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ ቤቱን ፡ ይበዘብዛል ።
፳፰ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ኃጢ
አት ፡ ሁሉ ፡ የሚሳደቡትም ፡ስድብ ፡ ሁሉ ፡ ይሰረ
፳፱ ይላቸዋል ፤ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ላይ ፡ የሚሳደብ ፡
ሁሉ ፡ ግን ፡ የዘላለም ፡ ኃጢአት ፡ ዕዳ ፡ ይሆን
በታል ፡ እንጂ ፡ ለዘላለም ፡ አይሰረይለትም ።
፴ ርኵስ ፡ መንፈስ ፡ አለበት ፡ ይሉ ፡ ነበርና ።
፴፩ እናቱና ፡ ወንድሞቹም ፡ መጡ ፡ በውጭም ፡
፴፪ ቆመው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ልከው ፡ አስጠሩት ። ብዙ ፡
ሰዎችም ፡ በዙሪያው ፡ ተቀምጠው ፡ ነበሩና ፦
እነሆ ፥ እናትህ ፡ ወንድሞችህም ፡ በውጭ ፡
፴፫ ቆመው ፡ ይፈልጉሃል ፡ አሉት ። መልሶም ፦
እናቴ ፡ ማን ፡ ናት ? ወንድሞቼስ ፡ እነ ፡ ማን ፡
፴፬ ናቸው ? አላቸው ። በዙሪያው ፡ ተቀምጠው ፡
ወደ ፡ ነበሩትም ፡ ተመለከተና ፦ እነሆ ፡ እናቴ ፡
፴፭ ወንድሞቼም ። የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡
የሚያደርግ ፡ ሁሉ ፥ እርሱ ፡ ወንድሜ ፡ ነው ፡
እኅቴም ፡ እናቴም ፡ አለ ።

ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ደግሞም ፡ በባሕር ፡ዳር ፡ ሊያስተምር ፡ጀመረ ።
አጅግ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ስለ ፡ ተሰ
በሰቡ ፡ እርሱ ፡ በታንኳ ፡ ገብቶ ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡
ተቀመጠ ፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በባሕር ፡ ዳር ፡ በም
፪ ድር ፡ ላይ ፡ ነበሩ ። በምሳሌም ፡ ብዙ ፡ ያስተም
ራቸው ፡ ነበር ፥ በትምህርቱም ፡ አላቸው ፦
፫፡፬ ስሙ ። እነሆ ፥ ዘሪ ፡ ሊዘራ ፡ ወጣ ። ሲዘራም ፡
አንዳንዱ ፡ በመንገድ ፡ ዳር ፡ ወደቀና ፡ ወፎች ፡

፪። ፳፯፤ ዘዳግ. ፭፥፲፬።

፫። ፩—፮፤ ማቴ. ፲፪፥፱—፲፬፤ ሉቃ. ፮፥፮—፲፩። ፮፤ ማቴ. ፳፪፥፲፮። ፯፥፰፤ ሉቃ. ፮፥፲፯፤፲፰። ፲፤ ም. ፭፥ ፳፱፤ ፮፥፶፮፤ ሉቃ. ፯፥፳፩። ፲፩፤ ም. ፩፥፳፬፤ ፭፥፯፤ ፲፭፥፴፱፤ ማቴ. ፰፥፳፱፤ ሉቃ. ፬፥፵፩፤ ዮሐ. ፩፥፵፱። ፲፪፤ ማቴ. ፲፪፥፲፮። ፲፫—፲፱፤ ማቴ. ፲፥፩፤ ሉቃ. ፮፥፲፪፤፲፫። ፲፮—፲፱፤ ማቴ. ፲፥፪—፬፤ ሉቃ. ፮፥፲፬—፲፮፤ የሐዋ. ፩፥፲፫። ፲፯፤ ማቴ. ፲፮፥፲፰፤ ዮሐ. ፩፥፵፪። ፳፪፤ ማቴ. ፱፥፴፬። ፳፪—፳፯፤ ማቴ. ፲፪፥፳፬—፳፱፤ ሉቃ. ፲፩፥ ፲፭—፳፪። ፳፰—፴፤ ማቴ. ፲፪፥፴፩፤፴፪። ፴፩—፴፭፤ ማቴ. ፲፪፥፵፮—፶፤ ሉቃ. ፰፥፲፱—፳፩።

፬። ፩—፱፤ ማቴ. ፲፫፥፩—፱፤ ሉቃ. ፰፥፬—፲፮።

፭፡ መጥተው ፡ በሉት ። ሌላውም ፡ ብዙ ፡ መሬት ፡ በሌለበት ፡ በጭንጫ ፡ ላይ ፡ ወደቀና ፡ ጥልቅ ፡
፮፡ መሬት ፡ ስላልነበረው ፡ ወዲያው ፡ በቀለ ፤ ፀሐ ይም ፡ ሲወጣ ፡ ጠወለገ ÷ ሥርም ፡ ስላልነበረው ፡
፯፡ ደረቀ ። ሌላውም ፡ በእሾህ ፡ መካከል ፡ ወደቀ ÷ እሾህም ፡ ወጣና ፡ አነቀው ÷ ፍሬም ፡ አልሰጠም ።
፰፡ ሌላውም ፡ በመልካም ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ወደቀና ፡ ወጥቶ ፡ አድጎ ፡ ፍሬ ፡ ሰጠ ÷ አንዱም ፡ ሠላሳ ፡ አን
፱፡ ዱም ፡ ስድሳ ፡ አንዱም ፡ መቶ ፡ አፈራ ። የሚ ሰማ ፡ ጆሮ ፡ ያለው ፡ ይስማ ፡ አለ ።

፲፡ ብቻውንም ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ÷ በዙሪያው ፡ የነበሩት ፡ ከአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ጋር ፡ ስለ ፡ ምሳሌው ፡ ጠየ
፲፩ ፲፪፡ ቁት ። እንዲህም ፡ አላቸው ፡— ለእናንተ ፡ የእግ ዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ ምሥጢር ፡ ማወቅ ፡ ተሰጥቶአችኋል ፤ በውጭ ፡ ላሉት ፡ ግን ÷

እያዩ ፡ እንዲያዩ ፡ እንዳይመለከቱም ÷
ሰምተውም ፡ እንዲሰሙ ፡ እንዳያስተው
ሉም ÷ እንዳይመለሱ ፡ ኃጢአታቸውም ፡
እንዳይሰረይላቸው ፡

፲፫፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በምሳሌ ፡ ይሆንባቸዋል ። አላቸ ውም ፡— ይህን ፡ ምሳሌ ፡ አታውቁምን ? እንዴ
፲፬፡ ትስ ፡ ምሳሌዎቹን ፡ ሁሉ ፡ ታውቃላችሁ ? ዘሪው ፡
፲፭፡ ቃሉን ፡ ይዘራል ። ቃልም ፡ በተዘራበት ፡ በመ ንገድ ፡ ዳር ፡ የሆኑት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ÷ በሰ ሙት ፡ ጊዜም ፡ ሰይጣን ፡ ወዲያው ፡ መጥቶ ፡ በልባቸው ፡ የተዘራውን ፡ ቃል ፡ ይወስዳል ።
፲፮፡ እንዲሁም ፡ በጭንጫ ፡ ላይ ፡ የተዘሩት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ÷ ቃሉንም ፡ ሰምተው ፡ ወዲያው ፡ በደ
፲፯፡ ስታ ፡ ይቀበሉታል ፤ ለጊዜውም ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በእነርሱ ፡ ሥር ፡ የላቸውም ÷ ኋላም ፡ በቃሉ ፡ ምክንያት ፡ መከራ ፡ ወይም ፡ ስደት ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡
፲፰፡ ወዲያው ፡ ይሰናከላሉ ። በእሾህም ፡ የተዘሩት ፡ ሌሎች ፡ ናቸው ÷ ቃሉን ፡ የሰሙት ፡ እነዚህ ፡
፲፱፡ ናቸው ÷ የዚህም ፡ ዓለም ፡ አሳብና ፡ የባለጠግነት ፡ ማታለል ፡ የሌላውም ፡ ነገር ፡ ምኞት ፡ ገብተው ፡
፳፡ ቃሉን ፡ ያንቃሉ ÷ የማያፈራም ፡ ይሆናል ። በመ ልካምም ፡ መሬት ፡ የተዘሩት ፡ ቃሉን ፡ ሰምተው ፡ የሚቀበሉት ፡ አንዱም ፡ ሠላሳ ፡ አንዱም ፡ ስድሳ ፡ አንዱም ፡ መቶ ፡ ፍሬ ፡ የሚያፈሩት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።

፳፩፡ እንዲህም ፡ አላቸው ፡— መብራትን ፡ ከዕን ቅብ ፡ ወይስ ፡ ከአልጋ ፡ በታች ፡ ሊያኖሩት ፡ ያመ ጡታልን ? በመቅረዝ ፡ ላይ ፡ ሊያኖሩት ፡ አይ
፳፪፡ ደለምን ? እንዲገለጥ ፡ ባይሆን ፡ የተሰወረ ፡ የለ ምና ፤ ወደ ፡ ግልጥ ፡ እንዲመጣ ፡ እንጂ ፡ የተሸ
፳፫፡ ሸገ ፡ የለም ። የሚሰማ ፡ ጆሮ ፡ ያለው ፡ ቢኖር ፡
፳፬፡ ይስማ ። አላቸውም ፡— ምን ፡ እንድትሰሙ ፡ ተጠበቁ ። በምትሰፍሩበት ፡ መስፈሪያ ፡ ይሰፈ ርላችኋል ፤ ለእናንተም ፡ ይጨመርላችኋል ።
፳፭፡ ላለው ፡ ይሰጠዋልና ፡ ከሌለውም ፡ ያው ፡ ያለው ፡ እንኳ ፡ ይወሰድበታል ።

፳፮፡ እርሱም ፡ አለ ፡— በምድር ፡ ዘርን ፡ እንደሚ ዘራ ፡ ሰው ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ እን
፳፯፡ ደዚህ ፡ ናት ፤ ሌሊትና ፡ ቀን ፡ ይተኛልም ፡ ይነ ሣልም ÷ እርሱም ፡ እንዴት ፡ እንደሚሆን ፡ ሳያ
፳፰፡ ውቅ ፡ ዘሩ ፡ ይበቅላል ፡ ያድግማል ። ምድሪ ቱም ፡ አውቃ ፡ በመጀመሪያ ፡ ቡቃያ ፡ ኋላም ፡ ዛላ ፡ ኋላም ፡ በዛላው ፡ ፍጹም ፡ ሰብል ፡ ታፈራ
፳፱፡ ለች ። ፍሬ ፡ ግን ፡ ሲበስል ፡ መከር ፡ ደርሶአልና ፡ ወዲያው ፡ ማጭድ ፡ ይልካል ።

፴፡ እርሱም ፡ አለ ፡— የእግዚአብሔርን ፡ መን ግሥት ፡ በምን ፡ እናስመስላታለን ? ወይስ ፡
፴፩፡ በምን ፡ ምሳሌ ፡ እንመስላታለን ? እንደ ፡ ሰና ፍጭ ፡ ቅንጣት ፡ ናት ÷ እርስዋም ፡ በምድር ፡ በተ ዘራች ፡ ጊዜ ፡ በምድር ፡ ካለ ፡ ዘር ፡ ሁሉ ፡ ታን
፴፪፡ ሳለች ፡ በተዘራችም ፡ ጊዜ ፡ ትወጣለች ፡ ከአት ክልትም ፡ ሁሉ ፡ የምትበልጥ ፡ ትሆናለች ÷ የሰ ማይ ፡ወፎችም ፡ በጥላዋ ፡ ሊሰፍሩ ፡ እስኪችሉ ፡ ታላላቅ ፡ ቅርንጫፎች ፡ ታደርጋለች ።

፴፫፡ መስማትም ፡ በሚችሉበት ፡ መጠን ፡ እንደ ዚህ ፡ በሚመስል ፡ በብዙ ፡ ምሳሌ ፡ ቃሉን ፡ ይነ
፴፬፡ ግራቸው ፡ ነበር ፤ ያለ ፡ ምሳሌ ፡ ግን ፡ አልነገራቸ ውም ÷ ለብቻቸውም ፡ ሲሆኑ ፡ ነገሩን ፡ ሁሉ ፡ ለገዛ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ይፈታላቸው ፡ ነበር ።

፴፭፡ በዚያም ፡ ቀን ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡— ወደ ፡ ማዶ ፡
፴፮፡ እንሻገር ፡ አላቸው ። ሕዝቡንም ፡ ትተው ፡ በታ ንኳ ፡ እንዳለ ፡ ወሰዱት ÷ ሌሎች ፡ ታንኳዎ
፴፯፡ ችም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበሩ ። ብርቱ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስም ፡ ተነሣና ፡ ውኃ ፡ በታንኳይቱ ፡ እስኪሞላ ፡ ድረስ ፡ ማዕበሉ ፡ በታንኳይቱ ፡ ይገባ ፡ ነበር ።
፴፰፡ እርሱም ፡ በስተኋላዋ ፡ ትራስ ፡ ተንተርሶ ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ፡ አንቅተውም ፡— መምህር ፡ ሆይ ÷ ስን
፴፱፡ ጠፋ ፡ አይገድህምን ? አሉት ። ነቅቶም ፡ ነፋ ሱን ፡ ገሠጸው ፡ ባሕሩንም ፡— ዝም ፡ በል ÷ ፀጥ ፡ በል ፡ አለው ። ነፋሱም ፡ ተወ ፡ ታላቅ ፡ ፀጥ
፵፡ ታም ፡ ሆነ ። እንዲህ ፡ የምትፈሩ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ነው ? እንዴትስ ፡ እምነት ፡ የላችሁም ? አላ
፵፩፡ ቸው ። እጅግም ፡ ፈሩና ፡— እንግዲህ ፡ ነፋስም ፡ ባሕርም ፡ የሚታዘዙለት ፡ ይህ ፡ ማን ፡ ነው ? ተባባሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ማዶም ፡ ወደ ፡ ጌርጌሴኖን ፡ አገር ፡
፪፡ መጡ ። ከታንኳይቱም ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ÷ ርኩስ ፡ መንፈስ ፡ የያዘው ፡ ሰው ፡ ከመቃብር ፡ ወጥቶ ፡
፫፡ ወዲያው ፡ ተገናኘው ፤ እርሱም ፡ በመቃብር ፡ ይኖር ፡ ነበር ÷ በሰንሰለትም ፡ ስንኳ ፡ ማንም ፡ ሊያስረው ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አይችልም ፡ ነበር ፤
፬፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ በእግር ፡ ብረትና ፡ በሰንሰለት ፡ ይታ ሰር ፡ ነበርና ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ ሰንሰለቱን ፡ ይበጣ

፬ ። ፲፪ ፤ ኢሳ. ፮ ÷ ፱ ፡ ፲ ። ፳፩—፳፭ ፤ ሉቃ. ፰ ÷ ፲፮—፲፰ ፤ ማቴ. ፭ ÷ ፲፭ ። ፳፪ ፤ ማቴ. ፲ ÷ ፳፮ ። ፳፬ ፤ ማቴ. ፯ ÷ ፪ ፤ ሉቃ. ፮ ÷ ፴፰ ። ፳፭ ፤ ማቴ. ፲፫ ÷ ፲፪ ፤ ሉቃ. ፲፱ ፡ ፳፮ ። ፴—፴፪ ፤ ማቴ. ፲፫ ÷ ፴፩ ፡ ፴፪ ፤ ሉቃ. ፲፫ ÷ ፲፰ ፡ ፲፱ ። ፴፫ ፡ ፴፬ ፤ ማቴ. ፲፫ ፡ ፴፬ ። ፴፭—፵፩ ፤ ማቴ. ፰ ÷ ፳፫—፳፯ ፤ ሉቃ. ፰ ÷ ፳፪—፳፭ ።

፭ ። ፩—፳፩ ፤ ማቴ. ፰ ÷ ፳፰—፱ ÷ ፩ ፤ ሉቃ. ፰ ÷ ፳፮—፵ ።

ጥስ፡ እግር፡ ብረቱንም፡ ይሰብብር፡ ነበር፥ ሊያ
፬ ሸንፈውም፡ የሚችል፡ አልነበረም፤ ሁልጊ
ዜም፡ ሌሊትና፡ ቀን፡ በመቃብርና፡ በተራራ፡
ሆኖ፡ ይጮኽ፡ ነበር፡ ሰውነቱንም፡ በድንጋይ፡
፭ ይቧጭር፡ ነበር። ኢየሱስንም፡ ከሩቅ፡ ባየ፡
፮ ጊዜ፡ ሮጠ፡ ሰገደለት፥ በታላቅ፡ ድምፅም፡ እየ
፯ ጮኸ፡— የልዑል፡ እግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ኢየ
ሱስ፡ ሆይ፥ ከአንተ፡ ጋር፡ ምን፡ አለኝ? እንዳ
ትሣቅየኝ፡ በእግዚአብሔር፡ እምልሃለሁ፡ አለ፤
፰ አንተ፡ ርኩስ፡ መንፈስ፥ ከዚህ፡ ሰው፡ ውጣ፡
፱ ብሎት፡ ነበርና። ስምህ፡ ማን፡ ነው? ብሎ፡
ጠየቀው። ብዙዎች፡ ነንና፡ ስሜ፡ ሌጌዎን፡ (1)
፲ ነው፡ አለው፥ ከአገርም፡ ውጭ፡ እንዳያሰዳ
፲፩ ቸው፡ አጥብቆ፡ ለመነው። በዚያም፡ በተራራ፡
ጥግ፡ ብዙ፡ የእሪያ፡ መንጋ፡ ይሰማራ፡ ነበርና፥—
፲፪ ወደ፡ እሪያዎቹ፡ እንድንገባ፡ ስደደን፡ ብለው፡
፲፫ ለመኑት። ኢየሱስም፡ ፈቀደላቸው። ርኩሳን፡
መናፍስቱም፡ ወጥተው፡ ወደ፡ እሪያዎቹ፡ ገቡ፥
ሁለት፡ ሺህም፡ የሚያህል፡ መንጋ፡ ከአፋፉ፡
ወደ፡ ባሕር፡ ተጣደፉና፡ በባሕር፡ ሰጠሙ።

፲፬ እረኞቹም፡ ሸሽተው፡ በአተማውና፡ በአገሩ፡
አወሩ፤ ነገሩም፡ ምን፡ እንደ፡ ሆነ፡ ለማየት፡
፲፭ መጡ። ወደ፡ ኢየሱስም፡ መጡ፥ አጋንንትም፡
ያደሩበትን፡ ሌጌዎንም፡ የነበረበትን፡ ሰው፡
ተቀምጦ፡ ለብሶም፡ ልቡም፡ ተመልሶ፡ አዩና፡
፲፮ ፈሩ። ያዩት፡ ሰዎችም፡ አጋንንት፡ ላደሩበት፡
ሰው፡ የሆነውንና፡ ስለ፡ እሪያዎቹ፡ ተረኩላቸው።
፲፯ ከአገራቸውም፡ እንዲሄድላቸው፡ ይለምኑት፡
፲፰ ጀመር። ወደ፡ ታንኳይቱም፡ በገባ፡ ጊዜ፡ አጋ
ንንት፡ አድረውበት፡ የነበረው፡ ሰው፡ ከእርሱ፡
፲፱ ጋር፡ እንዲኖር፡ ለመነው። ኢየሱስም፡ አልፈ
ቀደለትም፥ ነገር፡ ግን፡— ወደ፡ ቤትህ፡ በቤተ፡
ሰዎችህ፡ ዘንድ፡ ሂድህ፡ ጌታ፡ እንዴት፡ ያለ፡
ታላቅ፡ ነገር፡ እንዳደረገልህ፡ እንዴትስ፡ እንደ፡
፳ ማረህ፡ አውራላቸው፡ አለው። ሄዶም፡ ኢየ
ሱስ፡ እንዴት፡ ያለ፡ ታላቅ፡ ነገር፡ እንዳደረገ
ለት፡ አሥር፡ ከተማ፡ በሚባል፡ አገር፡ ይሰብክ፡
ጀመር፥ ሁሉም፡ ተደነቁ።

፳፩ ኢየሱስም፡ ደግሞ፡ በታንኳይቱ፡ ወደ፡ ማዶ፡
ከተሻገረ፡ በኋላ፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ ወደ፡ እርሱ፡
፳፪ ተሰበሰቡ፥ በባሕርም፡ አጠገብ፡ ነበረ። ኢያ
ኢሮስ፡ የተባለ፡ ከምኵራብ፡ አለቆች፡ አንዱ፡
መጣ፤ ባየውም፡ ጊዜ፡ በእግሩ፡ ላይ፡ ወደቀና፡—
፳፫ ታናሽቱ፡ ልጄ፡ ልትሞት፡ ተቃርባለችና፡ እንድ
ትድንና፡ በሕይወት፡ እንድትኖር፡ መጥተህ፡
እጆችህን፡ ጫንባት፡ ብሎ፡ አጥብቆ፡ ለመነው።
፳፬ ከእርሱም፡ ጋር፡ ሄደ። ብዙ፡ ሕዝብም፡ ተከ
ተሉት፡ አጋፉትም።

፳፭ ከአሥራ፡ ሁለት፡ ዓመትም፡ ጀምሮ፡ ደም፡
፳፮ የሚፈሳት፡ ሴት፡ ነበረች፥ ከብዙ፡ ባለ፡ መድ

(1) ሌጌዎን፡ ማለት፡ ጭፍራ፡ ማለት፡ ነው።

ኃኒቶችም፡ ብዙ፡ ተሣቀየች፤ ገንዘብዋንም፡
ሁሉ፡ ከስራ፡ ባሰበት፡ እንጂ፡ ምንም፡ አልተ
፳፯ ጠቀመችም፤ የኢየሱስንም፡ ወሬ፡ ሰምታ፡ በስ
ተኋላው፡ በሰዎች፡ መካከል፡ መጥታ፡ ልብሱን፡
፳፰ ዳሰሰች፥— ልብሱን፡ ብቻ፡ የዳሰስሁ፡ እንደ፡
፳፱ ሆን፡ እድናለሁ፡ ብላለችና። ወዲያውም፡ የደ
ምዋ፡ ምንጭ፡ ደረቀ፡ ከሥቃይዋም፡ እንደ፡
፴ ዳነች፡ በሰውነትዋ፡ አወቀች። ወዲያውም፡
ኢየሱስ፡ ከእርሱ፡ ኃይል፡ እንደ፡ ወጣ፡ በገዛ፡
ራሱ፡ አውቆ፡ በሕዝቡ፡ መካከል፡ ዞሮ፡ ብሎ፡—
፴፩ ልብሴን፡ የዳሰሰ፡ ማን፡ ነው? አለ። ደቀ፡ መዛ
ሙርቱም፡— ሕዝቡ፡ ሲያጋፉህ፡ እያየህ፡— ማን፡
፴፪ ዳሰሰኝ፡ ትላለህን? አሉት። ይህንም፡ ያደረገች
ውን፡ ለማየት፡ ዞር፡ ብሎ፡ ይመለከት፡ ነበር።
፴፫ ሴቲቱ፡ ግን፡ የተደረገላትን፡ ስላወቀች፥ እየ
ፈራች፡ እየተንቀጠቀጠችም፥ መጥታ፡ በፊቱ፡
፴፬ ተደፋች፡ እውነቱንም፡ ሁሉ፡ ነገረችው። እር
ሱም፡— ልጄ፡ ሆይ፥ እምነትሽ፡ አድኖሻል፤
በሰላም፡ ሂጂ፡ ከሥቃይሽም፡ ተፈወሽ፡ አላት።

፴፭ እርሱም፡ ገና፡ ሲናገር፡ ከምኵራብ፡ አለቃው፡
ቤት፡ ዘንድ፡ የመጡት፡— ልጅህ፡ ሞታለች፤
ስለ፡ ምን፡ መምህሩን፡ አሁን፡ ታደክመዋለህ?
፴፮ አሉት። ኢየሱስ፡ ግን፡ የተናገሩትን፡ ቃል፡
አድምጦ፡ ለምኵራብ፡ አለቃ፡— እመን፡ ብቻ፡
፴፯ እንጂ፡ አትፍራ፡ አለው። ከጴጥሮስም፡ ከያዕቆ
ብም፡ ከያዕቆብም፡ ወንድም፡ ከዮሐንስ፡ በቀር፡
፴፰ ማንም፡ እንዲከተለው፡ አልፈቀደም። ወደ፡
ምኵራብ፡ አለቃ፡ ቤትም፡ መጥቶ፡ ሰዎች፡
ሲንጫጩና፡ ሲያለቅሱ፡ ዋይታም፡ ሲያበዙ፡
፴፱ አየ፤ ገብቶም፡— ስለ፡ ምን፡ ትንጫጫላችሁ፡
ታለቅሱላችሁም? ብላቴናይቱ፡ ተኝታለች፡
፵ እንጂ፡ አልሞተችም፡ አላቸው። በጣምም፡
ሳቁበት። እርሱ፡ ግን፡ ሁሉን፡ አስወጥቶ፡ የብ
ላቴናይቱን፡ አባትና፡ እናትም፡ ከእርሱ፡ ጋር፡
የነበሩትንም፡ ይዞ፡ ብላቴናይቱ፡ ወዳለችበት፡
፵፩ ገባ። የብላቴናይቱንም፡ እጅ፡ ይዞ፡— ጣሊታ፡
ቁሚ፡ አላት፤ ፍችውም፡ አንቺ፡ ብላቴና፡ ተነሺ፡
፵፪ እልሻለሁ፡ ነው። ብላቴናይቱም፡ የአሥራ፡
ሁለት፡ ዓመት፡ ልጅ፡ ነበረችና፡ ወዲያው፡ ቆማ፡
ተመላለሰች። ወዲያውም፡ ታላቅ፡ መገረም፡
፵፫ ተገረሙ። ይህንም፡ ማንም፡ እንዳያውቅ፡ አጥ
ብቆ፡ አዘዛቸው፡— የምትበላውን፡ ስጡአት፡
አላቸው።

## ምዕራፍ፡ ፮።

፩ ከዚያም፡ ወጥቶ፡ ወደ፡ ገዛ፡ አገሩ፡ መጣ፡
፪ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ተከተሉት። ሰንበትም፡
በሆነ፡ ጊዜ፡ በምኵራብ፡ ያስተምር፡ ጀመር፤
ብዙዎችም፡ ሰምተው፡ ተገረሙና፡— እነዚህን፡
ነገሮች፡ ይህ፡ ከወዴት፡ አገኛቸው? ለዚህ፡ የተ
ሰጠችው፡ ጥበብ፡ ምንድር፡ ናት? በእጁም፡

፭። ፯፤ ም. ፫፥፲፩። ፳፪—፵፫፤ ማቴ. ፱፥፲፰—፳፮፤ ሉቃ. ፰፥፵፩—፶፮። ፴፬፤ ም. ፱፥፲። ፵፩፤ ሉቃ. ፯፥፲፬።
፵፫፤ ም. ፯፥፴፮። ፵፫፤ ም. ፱፥፱፤ ፲፩፥፵፰፤ ማቴ. ፲፯፥፱።

፮። ፩—፮፤ ማቴ. ፲፫፥፶፬—፶፰፤ ሉቃ. ፬፥፲፮—፴።

የሚደረጉ ፡ እንደነዚህ ፡ ያሉ ፡ ተአምራት ፡ ምን ድር ፡ ናቸው ? ፫ ይህስ ፡ ጸራቢው ፡ የማርያም ፡ ልጅ ፡ የያዕቆብም ፡ የዮሳም ፡ የይሁዳም ፡ የስምዖንም ፡ ወንድም ፡ አይደለምን ? እኅቶቹስ ፡ በዚህ ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ አይደሉምን ? አሉ ፤ ይሰናከሉበትም ፡ ነበር ። ፬ ኢየሱስም ፦ ነቢይ ፡ ከገዛ ፡ አገሩና ፡ ከገዛ ፡ ዘመዶቹ ፡ ከገዛ ፡ ቤቱም ፡ በቀር ፡ ሳይከበር ፡ አይቀርም ፡ አላቸው ። ፭ በዚያም ፡ በጥቂቶች ፡ ድውዮች ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ጭኖ ፡ ከመፈወስ ፡ በቀር ÷ ተአምር ፡ ሊያደርግ ፡ ምንም ፡ አል ቻለም ። ፮ ስለ ፡ አለማመናቸውም ፡ ተደነቀ ።

በመንደሮችም ፡ እያስተማረ ፡ ይዞር ፡ ነበር ።

፯ አሥራ ፡ ሁለቱንም ፡ወደ ፡ እርሱ ፡ ጠራ ፡ ሁለት ፡ ሁለቱንም ፡ ይልካቸው ፡ ጀመረ ÷ በርኩሳን ፡ ፰ መናፍስትም ፡ ላይ ፡ሥልጣን ፡ ሰጣቸው ÷ ለመንገድም ፡ ከበትር ፡ በቀር ፡ እንጀራም ፡ ቢሆን ፡ ከረጢትም ፡ ቢሆን ፡ መሐለቅም ፡ በመቀነታ ፱ ቸው ፡ ቢሆን ፡ እንዳይዙ ፡ አዘዛቸው ። በእግ ራችሁ ፡ጫማ ፡ አድርጉ ፡ እንጂ ፡ ሁለት ፡ እጀ ፲ ጠባብ ፡ አትልበሱ ፡ አለ ። በማናቸውም ፡ በፍራ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ብትገቡ ፡ ከዚያ ፡ እስክትወጡ ፡ ፲፩ ድረስ ፡ በዚያው ፡ ተቀመጡ ። ከማይቀበሉአች ሁና ፡ ከማይሰሙአችሁ ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ÷ ከዚያ ፡ ወጥታችሁ ፡ ምስክር ፡ ይሆንባቸው ፡ ዘንድ ፡ ከእ ግራችሁ ፡ በታች ፡ ያለውን ፡ ትቢያ ፡ አራግፉ ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ÷ ከዚያች ፡ከተማ ፡ ይልቅ ፡ ለሰዶምና ፡ ለገሞራ ፡ በፍርድ ፡ ቀን ፡ ይቀልላቸ ፲፪ ዋል ፡ አላቸው ። ወጥተውም ፡ ንስሐ ፡ እንዲገቡ ፡ ፲፫ ሰበኩ ÷ ብዙ ፡ አጋንንትንም ፡ አወጡ ÷ ብዙ ፡ ድውዮችንም ፡ ዘይት ፡ እየቀቡ ፡ ፈወሱአቸው ።

፲፬ ስሙም ፡ ተገልጦአልና ፡ ንጉሡ ፡ ሄሮድስ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፦ መጥምቁ ፡ ዮሐንስ ፡ ከሙታን ፡ ተነሥቶአል ፡ ስለዚህም ፡ ኃይል ፡ በእርሱ ፡ ይደ ፲፭ ረጋል ፡ አለ ። ሌሎችም ፦ ኤልያስ ፡ ነው ፡ አሉ ፤ ሌሎችም ፦ ከነቢያት ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ነቢይ ፡ ፲፮ ነው ፡ አሉ ። ሄሮድስ ፡ ግን ፡ ሰምቶ ፦ እኔ ፡ ራሱን ፡ ያስቈረጥሁት ፡ ዮሐንስ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ፲፯ እርሱ ፡ ከሙታን ፡ ተነሥቶአል ፡ አለ ። ሄሮድስ ፡ የወንድሙን ፡ የፊልጶስን ፡ሚስት ፡ ሄሮድያዳን ፡ አግብቶ ፡ ነበርና ፡ በእርስዋ ፡ ምክንያት ፡ ራሱ ፡ ልኮ ፡ ዮሐንስን ፡ አስይዞ ፡ በወኅኒ ፡ አሳስሮት ፡ ፲፰ ነበር ፤ ዮሐንስ ፡ ሄሮድስን ፦ የወንድምህ ፡ ሚስት ፡ ለአንተ ፡ ልትሆን ፡ አልተፈቀደም ፡ ፲፱ ይለው ፡ ነበርና ። ሄሮድያዳ ፡ ግን ፡ ተቃውማው ፡ ልትገድለው ፡ ትፈልግ ፡ ነበር ፡ አልቻለችም ፤ ፳ ሄሮድስ ፡ ዮሐንስ ፡ ጻድቅና ፡ ቅዱስ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አውቶ ፡ ይፈራውና ፡ ይጠባበቀው ፡ ነበር ፤ እርሱንም ፡ ሰምቶ ፡ በብዙ ፡ ነገር ፡ ያመነታ ፡ ነበር ፤ ፳፩ በደስታም ፡ ይሰማው ፡ ነበር ። ሄሮድስም ፡ በተወ ለደበት ፡ ቀን ፡ ለመኳንንቱና ፡ ለሻለቆቹ ፡ ለገሊ ላም ፡ ሹማምንት ፡ ግብር ፡ ባደረገ ፡ ጊዜ ፡ ምቹ ፡ ፳፪ ቀን ፡ሆነላትና ፡ የሄሮድያዳ ፡ ልጅ ፡ ገብታ ፡ በትዘ ፍን ፡ ሄሮድስንና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የተቀመጡትን ፡ ደስ ፡ አሰኘቻቸው ። ንጉሡም ፡ ብላቴናይቱን ፦ የምትወጂውን ፡ ሁሉ ፡ ለምኝኝ ፡ እሰጥሽማለሁ ፡ ፳፫ አላት ፤ የመንግሥቴ ፡ እኩሌታ ፡ በንኳ ፡ ቢሆን ፡ የምትለምኚውን ፡ ሁሉ ፡ እሰጥሻለሁ ፡ ብሎ ፡ ማለ ፳፬ ላት ። ወጥታም ፡ ለእናትዋ ፦ ምን ፡ ልለምነው ? አለች ። እርስዋም ፦ የመጥምቁን ፡ የዮሐን ፳፭ ስን ፡ ራስ ፡ አለች ። ወዲያውም ፡ ፈጥና ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ገብታ ፦ የመጥምቁን ፡ የዮሐንስን ፡ ራስ ፡ በወጭት ፡ አሁን ፡ ልትሰጠኝ ፡ እወዳለሁ ፡ ፳፮ ብላ ፡ ለመነችው ። ንጉሡም ፡ አጅግ ፡ አዘነ ፡ ስለ ፡ መሐላው ፡ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ስለ ፡ ተቀመ ፳፯ ጡት ፡ሊነሣት ፡ አልወደደም ። ወዲያውም ፡ ንጉሡ ፡ ባለ ፡ ወግ ፡ ልኮ ፡ራሱን ፡ እንዲያመጣ ፡ አዘዘው ። ሄዶም ፡ በወኅኒ ፡ ራሱን ፡ ቈረጠ ÷ ፳፰ ራሱንም ፡ በወጭት ፡ አምጥቶ ፡ ለብላቴናይቱ ፡ ሰጣት ÷ ብላቴናይቱም ፡ ለእናትዋ ፡ ሰጠች ። ፳፱ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ሰምተው ፡ መጡ ፡ በድኑ ንም ፡ ወስደው ፡ ቀበሩት ።

፴ ሐዋርያትም ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡ ተሰብስበው ፡ ያደረጉትንና ፡ ያስተማሩትን ፡ ሁሉ ፡ ነገሩት ። ፴፩ እናንተ ፡ ራሳችሁ ፡ ብቻችሁን ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ኑና ፡ ጥቂት ፡ ዕረፉ ፡ አላቸው ፤ የሚመጡና ፡ የሚሄዱ ፡ ብዙዎች ፡ነበሩና ÷ ለመብላት ፡ እንኳ ፡ ፴፪ ጊዜ ፡ አጡ ። በታንኳም ፡ ብቻቸውን ፡ ወደ ፡ ፴፫ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሄዱ ። ሰዎችም ፡ ሲሄዱ ፡ አዩአ ቸው ፡ ብዙዎችም ፡ አወቁአቸውና ፡ ከከተሞች ፡ ሁሉ ፡ በእግር ፡ እየሮጡ ፡ ወዲያ ፡ ቀደሙአቸው ፡ ፴፬ ወደ ፡ እርሱም ፡ ተሰበሰቡ ። ኢየሱስም ፡ ወጥቶ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ አየና ፡ እረኛ ፡ እንደሌላቸው ፡ በጎች ፡ ስለ ፡ ነበሩ ፡ አዘነላቸው ÷ ብዙም ፡ ነገር ፡ ፴፭ ያስተምራቸው ፡ ጀመር ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ብዙ ፡ ሰዓት ፡ ካለፈ ፡ በኋላ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀርበው ፦ ቦታው ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ነው ፡ ፴፮ አሁንም ፡ መሽቶአል ፤ የሚበሉት ፡ የላቸውምና ፡ በዙሪያ ፡ ወዳሉ ፡ ገጠሮችና ፡ መንደሮች ፡ ሄደው ፡ እንጀራ ፡ ለራሳቸው ፡ እንዲገዙ ፡ አሰናብታቸው ፡ ፴፯ አሉት ። እርሱ ፡ ግን ፡ መልሶ ፦ እናንተ ፡ የሚበ ሉትን ፡ ስጡአቸው ፡ አላቸው ። ሄደን ፡ እንጀራ ፡ በሁለት ፡ መቶ ፡ ዲናር ፡ እንግዛላቸውን ? እንዲ በሉም ፡ እንስጣቸውን ? አሉት ። ፴፰ እርሱም ፦ ስንት ፡ እንጀራ ፡ አላችሁ ? ሂዱና ፡ እዩ ፡ አላ ቸው ። ባወቁም ፡ ጊዜ ፦ አምስት ÷ ሁለትም ፡ ፴፱ ዓሣ ፡ አሉት ። ሁሉንም ፡ በየክፍሉ ፡ በለመለመ ፡ ሣር ፡ ላይ ፡ እንዲያስቀምጡአቸው ፡ አዘዛቸው ። ፵ መቶ ፡ መቶውና ፡ አምሳ ፡ አምሳው ፡ እየሆኑ ፡ ፵፩ በተራ ፡ በተራ ፡ ተቀመጡ ። አምስቱንም ፡ እን ጀራ ፡ ሁለቱንም ፡ ዓሣ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አሻ ቅቦ ፡ አየና ፡ ባረከ ÷ እንጀራውንም ፡ ቈርሶ ፡ እን ዲያቀርቡላቸው ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ሰጠ ÷

፮ ። ፮ — ፲፩ ፤ ማቴ. ፲ ፥ ፩ ፡ ፭ ፡ ፱ — ፲፭ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፩ — ፭ ። ፲፬ — ፳፱ ፤ ማቴ. ፲፬ ፥ ፩ — ፲፪ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፯ — ፱ ። ፲፭ ፤ ም. ፰ ፥ ፳፰ ። ፲፰ ፤ ዘሌዋ. ፲፰ ፥ ፲፮ ። ፴ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፲ ። ፴፩ — ፵፬ ፤ ማቴ. ፲፬ ፥ ፲፫ — ፳፩ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፲ — ፲፯ ፤ ዮሐ. ፮ ፥ ፩ — ፲፫ ። ፴፬ ፤ ም. ፰ ፥ ፱ — ፱ ፤ ማቴ. ፱ ፥ ፴፯ ።

፵፪ ሁለቱን ፡ ዓሣ ፡ ደግሞ ፡ ለሁሉ ፡ ከፈለ ። ሁሉም ፡
፵፫ በልተው ፡ ጠገቡ ፤ ከቍርስራሹም ፡ አሥራ ፡
ሁለት ፡ መሶብ ፡ የሞላ ፡ አነሡ ፡ ከዓሣውም ፡
፵፬ ደግሞ ። እንጀራውንም ፡ የበሉት ፡ ወንዶቹ ፡
አምስት ፡ ሺህ ፡ ነበሩ ።

፵፭ ወዲያውም ፡ ሕዝቡን ፡ ሲያሰናብት ፡ ሳለ ፡ ደቀ ፡
መዛሙርቱ ፡ በታንኳ ፡ ገብተው ፡ ወደ ፡ ማዶ ፡
ወደ ፡ ቤተ ፡ ሳይዳ ፡ እንዲቀድሙት ፡ ግድ ፡ አላ
፵፮ ቸው ። ካሰናበታቸውም ፡ በኋላ ፡ ሊጸልይ ፡ ወደ ፡
፵፯ ተራራ ፡ ወጣ ። በመሸም ፡ ጊዜ ፡ ታንኳይቱ ፡ በባ
ሕር ፡ መካከል ፡ ሳለች ፡ እርሱ ፡ ብቻውን ፡ በም
፵፰ ድር ፡ ላይ ፡ ነበረ ። ነፋስ ፡ ከወደ ፡ ፊታቸው ፡ ነበ
ረና ፡ እየቀዘፉ ፡ ሲጨነቁ ፡ አይቶ ፥ ከሌሊቱ ፡ በአ
ራተኛው ፡ ክፍል ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡ እየሄደ ፡ ወደ ፡
እነርሱ ፡ መጣ ፡ ሊያልፋቸውም ፡ ይወድ ፡ ነበር ።
፵፱ እነርሱ ፡ ግን ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡ ሲሄድ ፡ ባዩት ፡ ጊዜ ፡
፶ ምትሀት ፡ መስሎአቸውና ፡ ጮኹ ፤ ሁሉ ፡ አይተ
ውታልና ፥ ታወኩም ። ወዲያውም ፡ ተናገራቸ
ውና ፦ አይዞአችሁ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፥ አትፍሩ ፡ አላ
፶፩ ቸው ። ወደ ፡ እነርሱም ፡ ወደ ፡ ታንኳይቱ ፡ ገባ ፥
ነፋሱም ፡ ተወ ፡ በራሳቸውም ፡ ያለ ፡ መጠን ፡
፶፪ እጅግ ፡ ተገረሙ ፡ ስለ ፡ እንጀራው ፡ አላስተዋሉ
ምና ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ልባቸው ፡ ደንዝዞ ፡ ነበር ።

፶፫ ተሻግረውም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ወደ ፡ ጌንሴሬጥ ፡
፶፬ ደረሱ ፡ ታንኳይቱንም ፡ አስጠጉ ። ከታንኳይ
፶፭ ቱም ፡ ሲወጡ ፡ ወዲያው ፡ አውቀውት ፡ በዚያች ፡
አገር ፡ ሁሉ ፡ ዙሪያ ፡ ሮጡና ፡ እርሱ ፡ እንዳለ ፡
ወደ ፡ ሰሙበት ፡ ስፍራ ፡ ሕመምተኞችን ፡ በአ
፶፮ ልጋ ፡ ላይ ፡ ያመጡ ፡ ጀመር ። በገባበትም ፡ ስፍራ ፡
ሁሉ ፥ መንደርም ፡ ከተማም ፡ ገጠርም ፡ ቢሆን ፥
በገበያ ፡ ድውዮችን ፡ ያኖሩ ፡ ነበር ፤ የልብሱንም ፡
ጫፍ ፡ እንኳ ፡ ሊዳስሱ ፡ ይለምኑት ፡ ነበር ፤ የዳ
ሰሱትም ፡ ሁሉ ፡ ዳኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ፈሪሳውያንና ፡ ከጻፎች ፡ ወገን ፡ ከኢየሩሳሌም ፡
፪ የመጡትም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተሰበሰቡ ። ከደቀ ፡
መዛሙርቱም ፡ አንዳንድ ፡ በርኵስ ፡ ማለት ፡ ባል
፫ ታጠበ ፡ እጅ ፡ እንጀራ ፡ ሲበሉ ፡ አዩ ። ፈሪሳውያ
ንና ፡ አይሁድም ፡ ሁሉ ፡ የሽማግሎችን ፡ ወግ ፡
ሲጠብቁ ፡ እጃቸውን ፡ ደኅና ፡ አድርገው ፡ ሳይ
፬ ታጠቡ ፡ አይበሉምና ፥ ከገበያም ፡ ተመልሰው ፡
ካልታጠቡ ፡ አይበሉም ፥ ጽዋንም ፡ ማድጋንም ፡
የናስ ፡ ዕቃንም ፡ አልጋንም ፡ እንደ ፡ ማጠብ ፡
ሌላ ፡ ነገር ፡ ሊጠብቁት ፡ የተቀበሉት ፡ ብዙ ፡
፭ አለ ። ፈሪሳውያንም ፡ ጻፎችም ፦ ደቀ ፡ መዛሙ
ርትህ ፡ እንደ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ወግ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አይ
ሄዱም ? ነገር ፡ ግን ፡ እጃቸውን ፡ ሳይታጠቡ ፡
፮ እንጀራ ፡ ይበላሉ ፡ ብለው ፡ ጠየቁት ። እርሱ ፡
ግን ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ ኢሳይያስ ፡ ስለ ፡ እና
ንተ ፡ ስለ ፡ ግብዞች ፦
ይህ ፡ ሕዝብ ፡ በከንፈሩ ፡ ያከብረኛል ፡ ልቡ ፡
ግን ፡ ከእኔ ፡ በጣም ፡ የራቀ ፡ ነው ፡ የሰውም ፡ ፯
ሥርዓት ፡ የሆነን ፡ ትምህርት ፡ እያስተማሩ ፡
በከንቱ ፡ ያመልኩኛል ፡
ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ በእውነት ፡ ትንቢት ፡
ተናገረ ። የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ትታችሁ ፡ ፰
ጽዋን ፡ ማድጋንም ፡ እንደ ፡ ማጠብ ፡ የሰውን ፡
ወግ ፡ ትጠብቃላችሁ ፥ ይህንም ፡ የመሰለ ፡ ብዙ ፡
ሌላ ፡ ነገር ፡ ታደርጋላችሁ ።

እንዲህም ፡ አላቸው ፦ ወጋችሁን ፡ ትጠብቁ ፡ ፱
ዘንድ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ አጅግ ፡ ንቃ
ችኋል ። ሙሴ ፦ አባትህንና ፡ እናትህን ፡ አክ ፲
ብር ፡ ደግሞ ፦ አባቱን ፡ ወይም ፡ እናቱን ፡ የሰ
ደበ ፡ ፈጽሞ ፡ ይሙት ፡ ብሎአልና ። እናንተ ፡ ፲፩
ግን ፡ ትላላችሁ ፦ ሰው ፡ አባቱን ፡ ወይም ፡ እና
ቱን ፦ ከእኔ ፡ የምትጠቀምበት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡
ቍርባን ፡ ማለት ፡ መባ ፡ ነው ፡ ቢል ፥ ለአባቱና ፡ ፲፪
ለእናቱ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ሊያደርግ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡
አትፈቅዱለትም ፤ በሰተላለፋችሁትም ፡ ወግ ፡ ፲፫
የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ትሽራላችሁ ፤ እንደ
ዚሁም ፡ ይህን ፡ የሚመስል ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ ታደ
ርጋላችሁ ።

ደግሞም ፡ ሕዝቡን ፡ ጠርቶ ፦ ሁላችሁ ፡ እኔን ፡ ፲፬
ስሙ ፡ አስተውሉም ። ከሰው ፡ የሚወጡት ፡ ፲፭
ሰውን ፡ የሚያረክሱ ፡ ናቸው ፡ እንጂ ፡ ከሰው ፡
ውጭ ፡ የሚገባውስ ፡ ሊያረክሰው ፡ የሚችል ፡
ምንም ፡ የለም ። የሚሰማ ፡ ጆሮ ፡ ያለው ፡ ቢኖር ፡ ፲፮
ይስማ ፡ አላቸው ። ከሕዝቡ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ፲፯
ከገባ ፡ በኋላ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ምሳሌውን ፡
ጠየቁት ። እርሱም ፦ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፲፰
ዚህ ፡ የማታስተውሉ ፡ ናችሁን ? ከውጭ ፡ ወደ ፡
ሰው ፡ የሚገባ ፡ ሊያረክሰው ፡ ምንም ፡ እንዳይ
ችል ፡ አትመለከቱምን ? ወደ ፡ ሆድ ፡ ገብቶ ፡ ፲፱
ወደ ፡ እዳሪ ፡ ይወጣል ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ልብ ፡ አይ
ገባምና ፤ መብልን ፡ ሁሉ ፡ እያጠራ ፡ አላቸው ።
እርሱም ፡ አለ ፦ ከሰው ፡ የሚወጣው ፡ ሰውን ፡ ፳
የሚያረክስ ፡ ያ ፡ ነው ። ከውስጥ ፡ ከሰው ፡ ልብ ፡ ፳፩
የሚወጣ ፡ ክፉ ፡ አሳብ ፥ ዝሙት ፥ መስረቅ ፥ ፳፪
መግደል ፥ ምንዝርነት ፥ መጎምጀት ፥ ክፋት ፥
ተንኰል ፥ መዳራት ፥ ምቀኝነት ፥ ስድብ ፥ ትዕ
ቢት ፥ ስንፍና ፡ ናቸውና ፤ ይህ ፡ ክፉው ፡ ሁሉ ፡ ፳፫
ከውስጥ ፡ ይወጣል ፡ ሰውንም ፡ ያረክሰዋል ።

ከዚያም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ጢሮስና ፡ ወደ ፡ ፳፬
ሲዶና ፡ አገር ፡ ሄደ ። ወደ ፡ ቤትም ፡ ገብቶ ፡
ማንም ፡ እንዳያውቅበት ፡ ወደደ ፡ ሊሰወርም ፡
አልተቻለውም ፤ ወዲያው ፡ ግን ፡ ታናሺቱ ፡ ፳፭
ልጅዋ ፡ ርኵስ ፡ መንፈስ ፡ ያደረባት ፡ አንዲት ፡
ሴት ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ሰምታ ፡ መጣችና ፡ በእግሩ ፡
ላይ ፡ ተደፋች ፤ ሴቲቱም ፡ ግሪክ ፥ በትውልድዋም ፡ ፳፮
ሲሮፊኒቃዊት ፡ ነበረች ፤ ከልጅዋ ፡ ጋኔን ፡ ያወ
ጣላት ፡ ዘንድ ፡ ለመነችው ። ኢየሱስ ፡ ግን ፦ ፳፯
ልጆቹ ፡ በፊት ፡ ይጠግቡ ፡ ዘንድ ፡ ተዉ ፤ የልጆ
ቹን ፡ እንጀራ ፡ ይዞ ፡ ለቡችሎች ፡ መጣል ፡ አይ

፮ ። ፵፭ ፡ ፶፪ ፤ ማቴ. ፲፬ ፡ ፳፪ — ፴፫ ፤ ዮሐ. ፮ ፡ ፲፭ — ፳፩ ። ፶፫ — ፶፮ ፤ ማቴ. ፲፬ ፡ ፴፬ — ፴፮ ።
፯ ። ፩ — ፳፫ ፤ ማቴ. ፲፭ ፡ ፩ — ፳ ። ፮ ፡ ፯ ፤ ኢሳ. ፳፱ ፡ ፲፫ ። ፲ ፤ ዘፀ. ፳ ፡ ፲፪ ፤ ፳፩ ፡ ፲፯ ። ፳፬ ፤ ማቴ. ፲፭ ፡ ፳፩ — ፳፰ ።

፳፰፡ ገባምና ፡ እላት ። እርሰዋም ፡ መልሳ ፡— አዎን ፥ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ቡችሎች ፡ እንኳ ፡ ከማዕድ ፡ በታች ፡ ሆነው ፡ የልጆችን ፡ ፍርፋሪ ፡ ይበላሉ ፡ አለችው ።
፳፱፡ እርሱም ፡— ስለዚህ ፡ ቃልሽ ፡ ሂጂ ፡ ጋኔኑ ፡ ከል
፴፡ ጅሽ ፡ ወጥቶአል ፡ አላት ። ወደ ፡ ቤትዋም ፡ ሄዳ ፡ ጋኔኑ ፡ ወጥቶ ፡ ልጅዋም ፡ በአልጋ ፡ ላይ ፡ ተኝታ ፡ አገኘች ።

፴፩፡ ደግሞም ፡ ከጢሮስ ፡ አገር ፡ ወጥቶ ፡ በሲዶና ፡ አልፎ ፡ አሥር ፡ ከተማ ፡ በሚባል ፡ አገር ፡ መካ
፴፪፡ ከል ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ ባሕር ፡ መጣ ። ደንቆሮና ፡ ኰልታፋም ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አመጡ ፥
፴፫፡ እጁንም ፡ ይጭንበት ፡ ዘንድ ፡ ለመኑት ። ከሕ ዝቡም ፡ ለዩቶ ፡ ለብቻው ፡ ወሰደው ፥ ጣቶቹ ንም ፡ በጆሮቹ ፡ አገባ ፡ እንትፍም ፡ ብሎ ፡ መላ
፴፬፡ ሱን ፡ዳሰሰ ፤ ወደ ፡ ሰማይም ፡ አሻቅቦ ፡ አይቶ ፡ ቃተተና ፡— ኤፍታህ ፡ አለው ፥ እርሱም ፡ ተከ
፴፭፡ ፈት ፡ ማለት ፡ ነው ። ወዲያውም ፡ ጆሮቹ ፡ ተከ ፈቱ ፡ የመላሱም ፡ እስራት ፡ ተፈታ ፡ አጥርቶም ፡
፴፮፡ ተናገረ ። ለማንም ፡ እንዳይነግሩ ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ ባዘዛቸው ፡ መጠን ፡ ይልቅ ፡ እጅግ ፡
፴፯፡ አወሩት ። ያለ ፡ መጠንም ፡ ተገረሙና ፡— ሁሉን ፡ ደኅና ፡ አድርጎአል ፤ ደንቆሮችም ፡ እንዲሰሙ ፡ዲዳዎችም ፡ እንዲናገሩ ፡ ያደርጋል ፡ አሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ ደግሞ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ነበረ ፤ የሚበሉትም ፡ ስለሌላቸው ፡ ደቀ ፡ መዛሙር
፪፡ ቱን ፡ ጠርቶ ፡— ሕዝቡ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ እስካሁን ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ውለዋልና ፡ የሚበሉት ፡ ስለሌ
፫፡ ላቸው ፡ እራራላቸዋለሁ ፤ ከእነርሱም ፡ አንዳን ዶቹ ፡ ከሩቅ ፡ መጥተዋልና ፡ ጦማቸውን ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ ብሰናብታቸው ፡ በመንገድ ፡ ይዝላሉ ፡
፬፡ አላቸው ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡— በዚህ ፡ በም ድረ ፡ በዳ ፡ እንጀራ ፡ ከየት ፡ አግኝቶ ፡ ሰው ፡ እነዚህን ፡ ማጥገብ ፡ ይችላል ? ብለው ፡ መለሱ
፭፡ ለት ። እርሱም ፡— ስንት ፡ እንጀራ ፡ አላችሁ ? ብሎ ፡ ጠየቃቸው ፥ እነርሱም ፡— ሰባት ፡ አሉት ።
፮፡ ሕዝቡም ፡ በምድር ፡ እንዲቀመጡ ፡ አዘዘ ። ሰባቱንም ፡ እንጀራ ፡ ይዞ ፡ አመሰገነ ፥ ቆርሶም ፡ እንዲያቀርቡላቸው ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ሰጠ ፥
፯፡ ለሕዝቡም ፡ አቀረቡ ። ጥቂትም ፡ ትንንሽ ፡ ዓሣ ፡ ነበራቸው ፤ ባረከውም ፡ ይህንም ፡ ደግሞ ፡ እን
፰፡ ዲያቀርቡላቸው ፡ አዘዘ ። በሉም ፡ ጠገቡም ፥ የተረፈውንም ፡ ቍርስራሽ ፡ ሰባት ፡ ቅርጫት ፡
፱፡ አነሡ ። የበሉትም ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ያህል ፡ ነበሩ ።
፲፡ አሰናበታቸውም ። ወዲያውም ፡ ከደቀ ፡ መዛ ሙርቱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ታንኳይቱ ፡ ገብቶ ፡ ወደ ፡ ዳልማኑታ ፡ አገር ፡ መጣ ።

፲፩፡ ፈሪሳውያንም ፡ ወጡና ፡ ሊፈትኑት ፡ ከሰማይ ፡ ምልክት ፡ ከእርሱ ፡ ፈልገው ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይከራከሩ ፡ ጀመር ። በመንፈሱም ፡ እጅግ ፡ ቃተ
፲፪፡ ተና ፡— ይህ ፡ ትውልድ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ምልክት ፡ ይፈልጋል ? እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ለዚህ ፡ ትውልድ ፡ ምልክት ፡ አይሰጠውም ፡ አለ ። ትቶ
፲፫፡ አቸውም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ወደ ፡ ታንኳይቱ ፡ ገብቶ ፡ ወደ ፡ ማዶ ፡ ሄደ ።

፲፬፡ እንጀራ ፡ መያዝም ፡ ረሱ ፥ ለእነርሱም ፡ ከአ ንድ ፡ እንጀራ ፡ በቀር ፡ በታንኳይቱ ፡ አልነበራ
፲፭፡ ቸውም ። እርሱም ፡— ተጠንቀቁ ፤ ከፈሪሳው ያንና ፡ ከሄሮድስ ፡ እርሾ ፡ ተጠበቁ ፡ ብሎ ፡ አዘ
፲፮፡ ዛቸው ። እርስ ፡ በርሳቸውም ፡— እንጀራ ፡ ስለ
፲፯፡ ሌለን ፡ ይሆናል ፡ ብለው ፡ ተነጋገሩ ። ኢየሱ ስም ፡ አውቆ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— እንጀራ ፡ ስለሌላችሁ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትነጋገራላችሁ ? ገና ፡ አልተመለከታችሁምን ? አላስተዋላችሁምን ?
፲፰፡ ልባችሁስ ፡ ደንዝዞአልን ? ዓይን ፡ ሳላችሁ ፡ አታዩምን ? ጆሮስ ፡ ሳላችሁ ፡ አትሰሙምን ?
፲፱፡ ትዝስ ፡ አይላችሁምን ? አምስቱን ፡ እንጀራ ፡ ለአምስት ፡ ሺህ ፡ በቈረስሁ ፡ ጊዜ ፥ ቍርስራሽ ፡ የሞላ ፡ስንት ፡ መሶብ ፡ አነሣችሁ ? እነርሱም ፡—
፳፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ አሉት ። ሰባቱን ፡ እንጀራስ ፡ ለአራት ፡ ሺህ ፡ በቈረስሁ ፡ ጊዜ ፥ ቍርስራሽ ፡ የሞላ ፡ ስንት ፡ ቅርጫት ፡ አነሣችሁ ? እነር
፳፩፡ ሱም ፡— ሰባት ፡ አሉት ። ገና ፡ አላስተዋላችሁ ምን ? አላቸው ።

፳፪፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ሳይዳም ፡ መጡ ። ዕውርም ፡
፳፫፡ አመጡለት ፥ እንዲዳስሰውም ፡ ለመኑት ። ዕው ሩንም ፡ እጁን ፡ ይዞ ፡ ከመንደር ፡ ውጭ ፡ አወ ጣው ፥ በዓይኑም ፡ ተፍቶበት ፡ እጁንም ፡ ጭኖ በት ፡— አንዳች ፡ታያለህን ? ብሎ ፡ ጠየቀው ።
፳፬፡ አሻቅቦም ፡— ሰዎች ፡ እንደ ፡ ዛፍ ፡ ሲመላለሱ ፡
፳፭፡ አያለሁ ፡ አለ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ደግሞ ፡ እጁን ፡ በዓይኑ ፡ ላይ ፡ጫነበት ፡ አጥርቶም ፡ አየ ፡ ዳነም ፡
፳፮፡ ከሩቅም ፡ሳይቀር ፡ ሁሉን ፡ ተመለከተ ። ወደ ፡ ቤቱም ፡ሰደደውና ፡— ወደ ፡ መንደሩ ፡ አትግባ ፡ በመንደሩም ፡ ለማንም ፡ አንዳች ፡ አትናገር ፡ አለው ።

፳፯፡ ኢየሱስና ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ በፊልጶስ ፡ ቂሣርያ ፡ ወዳሉ ፡ መንደሮች ፡ ወጡ ፡ በመንገ ድም ፡— ሰዎች ፡ እኔ ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ይላሉ ? ብሎ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ ጠየቃቸው ።
፳፰፡ እነርሱም ፡— መጥምቁ ፡ ዮሐንስ ፥ ሌሎችም ፡ ኤልያስ ፥ ሌሎችም ፡ ከነቢያት ፡ አንዱ ፡ ብለው ፡
፳፱፡ ነገሩት ። እናንተስ ፡ እኔ ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ትላላችሁ ? ብሎ ፡ ጠየቃቸው ። ጴጥሮስም ፡— አንተ ፡ ክርስቶስ ፡ ነህ ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ። ስለ ፡
፴፡ እርሱም ፡ ለማንም ፡ እንዳይናገሩ ፡ አዘዛቸው ።
፴፩፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ብዙ ፡ መከራ ፡ ሊቀበል ፥ ከሽ

፯ ። ፴፩—፴፯ ፤ ማቴ. ፲፭ ፥ ፳፱—፴፩ ። ፴፫ ፤ ምዕ. ፰ ፥ ፳፫ ። ፴፭ ፤ ማቴ. ፳ ፥ ፱ ።

፰ ። ፩—፲ ፤ ምዕ. ፮ ፥ ፴፬—፵፬ ፤ ማቴ. ፲፭ ፥ ፴፪—፴፱ ። ፲፩—፳፩ ፤ ማቴ. ፲፮ ፥ ፩—፲፪ ፤ ሉቃ. ፲፪ ፥ ፶፬ ። ፲፩ ፤ ሉቃ. ፲፩ ፥ ፲፮ ። ፲፱ ፤ ምዕ. ፮ ፥ ፵፩—፵፬ ። ፳፫ ፤ ምዕ. ፯ ፥ ፴፫ ። ፳፮ ፤ ማቴ. ፰ ፥ ፬ ። ፳፯—፳፱ ፤ ማቴ. ፲፮ ፥ ፲፫—፲፮ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፲፰—፳ ። ፳፰ ፤ ምዕ. ፮ ፥ ፲፭ ። ፴ ፤ ማቴ. ፲፮ ፥ ፳ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፳፩ ። ፴፩—፱ ፥ ፩ ፤ ማቴ. ፲፮ ፥ ፳፩—፳፰ ፤ ሉቃ. ፱ ፥ ፳፪—፳፯ ። ፴፩ ፤ ምዕ. ፱ ፥ ፴፩ ፤ ፲ ፥ ፴፬ ፤ ዮሐ. ፲፪ ፥ ፴፬ ፤ ፴፫ ።

ማግሌዎችም ፡ ከካህናት ፡ አለቆችም ፡ ከጻፎችም ፡
ሊጣል ፥ ሊገደልም ፡ ከሦስት ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡
ሊነሣ ፡ እንዲገባው ፡ ያስተምራቸው ፡ ጀመር ፤
፴፪ ቃሉንም ፡ ገልጦ ፡ ይናገር ፡ ነበር ። ጴጥሮስም ፡
ወደ ፡ እርሱ ፡ ወስዶ ፡ ይገሥጸው ፡ ጀመር ።
፴፫ እርሱ ፡ ግን ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱንም ፡
አይቶ ፡ ጴጥሮስን ፡ ገሠጸውና ፦ ወደ ፡ ኋላዬ ፡
ሂድ ፥ አንተ ፡ ሰይጣን ፤ የሰውን ፡ እንጂ ፡ የእግ
ዚአብሔርን ፡ ነገር ፡ አታስብምና ፡ አለው ።
፴፬ ሕዝቡንም ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ጋር ፡ ጠርቶ ፡
እንዲህ ፡ አላቸው ፦ በኋላዬ ፡ ሊመጣ ፡ የሚ
ወድ ፡ ቢኖር ፥ ራሱን ፡ ይካድ ፡ መስቀሉንም ፡
፴፭ ተሸክሞ ፡ ይከተለኝ ። ነፍሱን ፡ ሊያድን ፡ የሚ
ወድ ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋታልና ፥ ስለ ፡ እኔና ፡ ስለ ፡
ወንጌል ፡ ነፍሱን ፡ የሚያጠፋ ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ያድ
፴፮ ናታል ። ሰው ፡ ዓለምን ፡ ሁሉ ፡ ቢያተርፍ ፡ ነፍ
ሱንም ፡ ቢያጐድል ፡ ምን ፡ ይጠቅመዋል ?
፴፯ ሰውስ ፡ ስለ ፡ ነፍሱ ፡ ቤዛ ፡ ምን ፡ ይሰጣል ?
፴፰ በዚህም ፡ በዘማዊና ፡ በኃጢአተኛ ፡ ትውልድ ፡
መካከል ፡ በእኔና ፡ በቃሌ ፡ የሚያፍር ፡ ሁሉ ፥
የሰው ፡ ልጅ ፡ ደግሞ ፡ በአባቱ ፡ ክብር ፡ ከቅዱ
ሳን ፡ መላእክት ፡ ጋር ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ በእርሱ ፡
ያፍርበታል ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ በዚህ ፡ ከቆሙት ፡ ሰዎች ፡
የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ በኃይል ፡ ስት
መጣ ፡ እስኪያዩ ፡ ድረስ ፥ ሞትን ፡ የማይቀምሱ ፡
አንዳንዶች ፡ አሉ ፡ አላቸው ።
፪ ከስድስት ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ኢየሱስ ፡ ጴጥሮስ
ንና ፡ ያዕቆብን ፡ ዮሐንስንም ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ረጅም ፡
ተራራ ፡ ብቻቸውን ፡ አወጣቸው ። በፊታቸ
፫ ውም ፡ ተለወጠ ፥ ልብሱም ፡ አንጸባረቀ ፤ አጣ
ቢም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እንደዚያ ፡ ሊያነጣው ፡
፬ እስከማይችል ፡ በጣም ፡ ነጭ ፡ ሆነ ። ኤልያስና ፡
ሙሴም ፡ ታዩአቸው ፥ ከኢየሱስም ፡ ጋር ፡ ይነጋ
፭ ገሩ ፡ ነበር ። ጴጥሮስም ፡ መልሶ ፡ ኢየሱስን ፦
መምህር ፡ ሆይ ፥ በዚህ ፡ መሆን ፡ ለእኛ ፡ መል
ካም ፡ ነውና ፡ አንድ ፡ ለአንተ ፡ አንድም ፡ ለሙሴ ፡
አንድም ፡ ለኤልያስ ፡ ሦስት ፡ዳሶች ፡ እንሥራ ፡
፮ አለው ። እጅግ ፡ ስለ ፡ ፈሩ ፡ የሚለውን ፡ አያው
፯ ቅም ፡ ነበር ። ደመናም ፡ መጥቶ ፡ ጋረዳቸው ፥
ከደመናውም ፦ የምወደው ፡ ልጄ ፡ ይህ ፡ ነው ፥
፰ እርሱን ፡ ስሙት ፡ የሚል ፡ድምፅ ፡ መጣ ። ድን
ገትም ፡ ዞረው ፡ ሲመለከቱ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ከኢ
የሱስ ፡ ብቻ ፡ በቀር ፡ ማንንም ፡ አላዩም ።
፱ ከተራራውም ፡ ሲወርዱ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ከሙ
ታን ፡ እስኪነሣ ፡ ድረስ ፡ ያዩትን ፡ ለማንም ፡ እን
፲ ዳይነግሩ ፡ አዘዛቸው ። ቃሉንም ፡ ይዘው ፦
ከሙታን ፡ መነሣት ፡ ምንድር ፡ ነው ? እያሉ ፡
፲፩ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተጠያየቁ ። እነርሱም ፦
ኤልያስ ፡ አስቀድሞ ፡ ሊመጣ ፡ እንዲገባው ፡
ጻፎች ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይላሉ ? ብለው ፡ ጠየቁት ።
፲፪ እርሱም ፡ መልሶ ፦ ኤልያስማ ፡ አስቀድሞ ፡
ይመጣል ፡ ሁሉንም ፡ ያቀናናል ፤ ስለ ፡ ሰው ፡
ልጅም ፡ እንዴት ፡ ተብሎ ፡ ተጽፎአል ? ብዙ ፡
፲፫ መከራ ፡ እንዲቀበል ፡ እንዲናቅም ። ነገር ፡ ግን ፡
እላችኋለሁ ፥ ኤልያስ ፡ ደግሞ ፡ መጥቶአል ፥
ስለ ፡ እርሱም ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ የወደዱትን ፡ ሁሉ ፡
አደረጉበት ፡ አላቸው ።
፲፬ ወደ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡
ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ሲከቡአቸው ፡ ጻፎችም ፡ ከእነርሱ ፡
፲፭ ጋር ፡ ሲከራከሩ ፡ አየ ። ወዲያውም ፡ ሕዝቡ ፡
ሁሉ ፡ ባዩት ፡ ጊዜ ፡ ደነገጡ ፥ ወደ ፡ እርሱም ፡
፲፮ ሮጠው ፡ እጅ ፡ ነሡት ። ጻፎችንም ፦ ስለ ፡
ምን ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ትከራከራላችሁ ? ብሎ ፡
፲፯ ጠየቃቸው ። ከሕዝቡ ፡ አንዱ ፡ መልሶ ፦
መምህር ፡ ሆይ ፥ ዲዳ ፡ መንፈስ ፡ ያደረበትን ፡
፲፰ ልጄን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ አምጥቼአለሁ ፤ በያዘውም ፡
ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ ይጥለዋል ፤ አረፋም ፡ ይደፍቃል ፥
ጥርሱንም ፡ ያፏጫል ፡ ይደርቃልም ፤ እንዲያወ
ጡለትም ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርትህ ፡ ነገርኋቸው ፥
፲፱ አልቻሉምም ፡ አለው ። እርሱም ፡ መልሶ ፦
የማታምን ፡ ትውልድ ፡ ሆይ ፥ እስከ ፡ መቼ ፡ ከእ
ናንተ ፡ ጋር ፡ እኖራለሁ ? እስከ ፡ መቼስ ፡ እታ
ገሣችኋለሁ ? ወደ ፡ እኔ ፡ አምጡት ፡ አላቸው ።
፳ ወደ ፡ እርሱም ፡ አመጡት ። እርሱንም ፡ ባየ ፡
ጊዜ ፡ ያ ፡ መንፈስ ፡ ወዲያው ፡ አንፈራገጠው ፤
ወደ ፡ ምድርም ፡ ወድቆ ፡ አረፋ ፡ እየደፈቀ ፡ ተን
፳፩ ፈራፈረ ። አባቱንም ፦ ይህ ፡ ከያዘው ፡ ስንት ፡
ዘመን ፡ ነው ? ብሎ ፡ ጠየቀው ። እርሱም ፦
፳፪ ከሕፃንነቱ ፡ ጀምሮ ፡ ነው ፤ ብዙ ፡ ጊዜም ፡ ሊያ
ጠፋው ፡ ወደ ፡ እሳትም ፡ ወደ ፡ ውኃም ፡ ጣለው ፤
ቢቻልህ ፡ ግን ፡ እዘንልን ፡ እርዳንም ፡ አለው ።
፳፫ ኢየሱስም ፦ ቢቻልህ ፡ ትላለህ ፤ ለሚያምን ፡
፳፬ ሁሉ ፡ ይቻላል ፡ አለው ። ወዲያውም ፡ የብላ
ቴናው ፡ አባት ፡ ጮኸ ፦ አምናለሁ ፤ አለማመ
፳፭ ኔን ፡ እርዳው ፡ አለ ። ኢየሱስም ፡ ሕዝቡ ፡ እንደ ፡
ገና ፡ ሲራወጥ ፡ አይቶ ፡ርኩሱን ፡ መንፈስ ፡ ገሥ
ጸና ፦ አንተ ፡ ዲዳ ፡ደንቆሮም ፡ መንፈስ ፥ እኔ ፡
እዝዝሃለሁ ፥ ከእርሱ ፡ ውጣ ፡ አንግዲህም ፡ አትግ
፳፮ ባበት ፡ አለው ። ጮኸም ፡ እጅግም ፡ አንፈራግ
ጦት ፡ ወጣ ፤ ብዙዎችም ፦ ሞተ ፡ እስኪሉ ፡
፳፯ ድረስ ፡ እንደ ፡ ሙት ፡ ሆነ ። ኢየሱስ ፡ ግን ፡
፳፰ እጁን ፡ ይዞ ፡ አስነሣው ፡ ቆመም ። ወደ ፡ ቤትም ፡
ከገባ ፡ በኋላ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፦ እኛ ፡ ልናወ
ጣው ፡ ያልቻልን ፡ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብለው ፡
፳፱ ብቻውን ፡ ጠየቁት ። ይህ ፡ወገን ፡ በጸሎትና ፡
በጦም ፡ ካልሆነ ፡ በምንም ፡ ሊወጣ ፡ አይችልም ፡
አላቸው ።

፰ ። [illegible]

፱ ። [illegible]

፱፥፴ ከዚያም ፡ ወጥተው ፡ በገሊላ ፡ በኩል ፡ አለፉ ፤ ደቀ ፡ መዛሙርቱንም ፡ ያስተምር ፡ ስለ ፡ ነበር ፡ ማንም ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፡ አልወደደም ፤ ለእነርሱም ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ በሰዎች ፡ እጅ ፡ አልፎ ፡ ይሰጣል ፥ ይገድሉትማል ፥ ተገድሎም ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ይነሣል ፡ ይላቸው ፡ ነበር ። ፴፩ እነርሱም ፡ ነገሩን ፡ አላስተዋሉም ፥ እንዲጠይቁትም ፡ ፈሩ ።

፴፫ ወደ ፡ ቅፍርናሆምም ፡ መጣ ። በቤትም ፡ ሆኖ ፡— በመንገድ ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ምን ፡ ፴፬ ተነጋገራችሁ ? ብሎ ፡ ጠየቃቸው ። እነርሱ ፡ ግን ፡ በመንገድ ፡— ከሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ ማን ፡ ፴፭ ይሆን ? ተባብለው ፡ ነበርና ፡ ዝም ፡ አሉ ። ተቀምጦም ፡ አሥራ ፡ ሁለቱን ፡ ጠርቶ ፡— ሰው ፡ ፊተኛ ፡ ሊሆን ፡ ቢወድ ፡ ከሁሉ ፡ በኋላ ፡ የሁ ፴፮ ሉም ፡ አገልጋይ ፡ ይሁን ፡ አላቸው ። ሕፃንም ፡ ይዞ ፡ በመካከላቸው ፡ አቆመው ፡ አቅፎም ፡— ፴፯ እንደዚህ ፡ ካሉ ፡ ሕፃናት ፡ አንዱን ፡ በስሜ ፡ የሚቀበል ፡ ሁሉ ፡ እኔን ፡ ይቀበላል ፤ የሚቀበለኝም ፡ ሁሉ ፡ የላከኝን ፡ እንጂ ፡ እኔን ፡ አይቀበልም ፡ አላቸው ።

፴፰ ዮሐንስ ፡ መልሶ ፡— መምህር ፡ ሆይ ፥ አንድ ፡ ሰው ፡ በስምህ ፡ አጋንንትን ፡ ሲያወጣ ፡ አየነው ፥ ፴፱ ስለማይከተለንም ፡ ከለከልነው ፡ አለው ። ኢየሱስ ፡ ግን ፡ አለ ፡— በስሜ ፡ ተአምር ፡ ሠርቶ ፡ በቶሎ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ መናገር ፡ የሚችል ፡ ፵ ማንም ፡ የለምና ፡ አትከልክሉት ፤ የማይቃወ ፵፩ መን ፡ እርሱ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ነውና ። የክርስቶስ ፡ ስለ ፡ ሆናችሁ ፡ በስሜ ፡ ጽዋ ፡ ውኃ ፡ የሚያጠጣችሁ ፡ ሁሉ ፥ ዋጋው ፡ እንዳይጠፋበት ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ።

፵፪ በእኔም ፡ ከሚያምኑት ፡ ከእነዚህ ፡ ከታናናሾቹ ፡ አንዱን ፡ የሚያሰናክል ፡ ሁሉ ፡ ትልቅ ፡ የወፍጮ ፡ ድንጋይ ፡ በአንገቱ ፡ ታስሮ ፡ ወደ ፡ ፵፫፡፵፬ ባሕር ፡ ቢጣል ፡ ይሻለው ፡ ነበር ። እጅህ ፡ ብታሰናክልህ ፡ ቍረጣት ፤ ሁለት ፡ እጅ ፡ ኖሮህ ፡ ትላቸው ፡ ወደማይሞትበት ፡ እሳቱም ፡ ወደማይጠፋበት ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ወደማይጠፋ ፡ እሳት ፡ ከመሄድ ፡ ጕንድሽ ፡ ሆነህ ፡ ወደ ፡ ሕይወት ፡ ፵፭፡፵፮ መግባት ፡ ይሻላል ። እግርህ ፡ ብታሰናክልህ ፡ ቍረጣት ፤ ሁለት ፡ እግር ፡ ኖሮህ ፡ ትላቸው ፡ ወደ ማይሞትበት ፡ እሳቱም ፡ ወደማይጠፋበት ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ወደማይጠፋ ፡ እሳት ፡ ከመጣል ፡ አንካሳ ፡ ሆነህ ፡ ወደ ፡ ሕይወት ፡ መግባት ፡ ይሻልሃል ። ፵፯፡፵፰ ዓይንህ ፡ ብታሰናክልህ ፡ አውጣት ፤ ሁለት ፡ ዓይን ፡ ኖሮህ ፡ ትላቸው ፡ ወደማይሞትበት ፡ እሳቱም ፡ ወደማይጠፋበት ፡ ወደ ፡ ገሃነመ ፡ እሳት ፡ ከመጣል ፡ አንዲት ፡ ዓይን ፡ ኖሮህ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ መግባት ፡ ይሻልሃል ። ፵፱ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በእሳት ፡ ይቀመማልና ፥ መሥዋዕትም ፡ ሁሉ ፡ በጨው ፡ ይቀመማል ። ፶ ጨው ፡ መልካም ፡ ነው ፤ ጨው ፡ ግን ፡ አልጫ ፡ ቢሆን ፡ በምን ፡ ታጣፍጡታላችሁ ? በነፍሳችሁ ፡ ጨው ፡ ይኑርባችሁ ፥ እርስ ፡ በርሳችሁም ፡ ተስማሙ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ ከዚያም ፡ ተነሥቶ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ አገር ፡ መጣ ፥ ደግሞም ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተሰበሰቡ ፡ እንደ ፡ ልማዱም ፡ ደግሞ ፡ ያስተምራቸው ፡ ነበር ።

፪ ፈሪሳውያንም ፡ ቀርበው ፡— ሰው ፡ ሚስቱን ፡ ሊፈታ ፡ ተፈቅዶለታልን ? ብለው ፡ ሊፈትኑት ፡ ጠየቁት ። ፫ እርሱ ፡ ግን ፡ መልሶ ፡— ሙሴ ፡ ምን ፡ ፬ አዘዛችሁ ? አላቸው ። እነርሱም ፡— ሙሴስ ፡ የፍችዋን ፡ ጽሕፈት ፡ ጽፎ ፡ እንዲፈታት ፡ ፈቀደ ፡ ፭ አሉ ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— ስለ ፡ ልባችሁ ፡ ጥንካሬ ፡ ይህችን ፡ ትእዛዝ ፡ ጻፈ ፮ ላችሁ ። ከፍጥረት ፡ መጀመሪያ ፡ ግን ፡ እግዚአ ፯ ብሔር ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ አደረጋቸው ፤ ስለዚህ ፡ ሰው ፡ አባቱንና ፡ እናቱን ፡ ይተዋል ፡ ከሚስቱም ፡ ፰ ጋር ፡ ይተባበራል ፥ ሁለቱም ፡ አንድ ፡ ሥጋ ፡ ይሆናሉ ፤ ስለዚህ ፡ አንድ ፡ ሥጋ ፡ ናቸው ፡ እንጂ ፡ ፱ ወደ ፡ ፊት ፡ ሁለት ፡ አይደሉም ። እግዚአብሔር ፡ ያጣመረውን ፡ እንግዲህ ፡ ሰው ፡ አይለየው ።

፲ በቤትም ፡ ደግሞ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ስለዚህ ፡ ፲፩ ነገር ፡ ጠየቁት ። እርሱም ፡— ሚስቱን ፡ ፈትቶ ፡ ሌላ ፡ የሚያገባ ፡ ሁሉ ፡ በእርስዋ ፡ ላይ ፡ ያመነዝ ፲፪ ራል ፤ እርስዋም ፡ ባልዋን ፡ ፈትታ ፡ ሌላ ፡ ብታገባ ፡ ታመነዝራለች ፡ አላቸው ።

፲፫ እንዲዳስሳቸውም ፡ ሕፃናትን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አመጡ ፤ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ያመጡአቸውን ፡ ፲፬ ገሠጹአቸው ። ኢየሱስ ፡ ግን ፡ አይቶ ፡ ተቈጣና ፡— ሕፃናትን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይመጡ ፡ ዘንድ ፡ ተዉ ፡ አትከልክሉአቸው ፤ የእግዚአብሔር ፡ ፲፭ መንግሥት ፡ እንደነዚህ ፡ ላሉት ፡ ናትና ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ፤ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ እንደ ፡ ሕፃን ፡ የማይቀበላት ፡ ሁሉ ፡ ከቶ ፡ ፲፮ አይገባባትም ፡ አላቸው ። አቀፋቸውም ፡ እጁንም ፡ ጭኖ ፡ ባረካቸው ።

፲፯ እርሱም ፡ በመንገድ ፡ ሲወጣ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ሮጦ ፡ ተንበረከከለትና ፡— ቸር ፡ መምህር ፡ ሆይ ፥ የዘላለም ፡ ሕይወትን ፡ እወርስ ፡ ዘንድ ፡ ምን ፡ ላድርግ ? ብሎ ፡ ጠየቀው ። ፲፰ ኢየሱስም ፡— ስለ ፡ ምን ፡ ቸር ፡ ትለኛለህ ? ከአንዱ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በቀር ፡ ቸር ፡ ማንም ፡

፱ ። ፴—፴፪ ፡ ማቴ. ፲፯ ፡ ፳፪ ፡ ፳፫ ፤ ሉቃ. ፱ ፡ ፵፬—፵፭ ። ፴፩ ፡ ም. ፰ ፡ ፴፩ ። ፴፫—፴፯ ፡ ማቴ. ፲፰ ፡ ፩—፭ ፤ ሉቃ. ፱ ፡ ፵፮—፵፰ ። ፴፭ ፡ ማቴ. ፳ ፡ ፳፮ ፡ ፳፯ ፤ ሉቃ. ፳፪ ፡ ፳፮ ። ፴፯ ፡ ማቴ. ፲ ፡ ፵ ። ፴፰—፵ ፡ ሉቃ. ፱ ፡ ፵፱ ፡ ፶ ። ፵ ፡ ማቴ. ፲፪ ፡ ፴ ። ፵፩ ፡ ማቴ. ፲ ፡ ፵፪ ። ፵፪ ፡ ማቴ. ፲፰ ፡ ፮ ። ፵፫—፵፰ ፡ ማቴ. ፭ ፡ ፳፱ ፡ ፴ ፤ ፲፰ ፡ ፰ ፡ ፱ ። ፵፱ ፡ ዘሌዋ. ፪ ፡ ፲፫ ። ፶ ፡ ማቴ. ፭ ፡ ፲፫ ፤ ሉቃ. ፲፬ ፡ ፴፬ ።

፲ ። ፩—፲፪ ፡ ማቴ. ፲፱ ፡ ፩—፱ ። ፬ ፡ ዘዳግ. ፳፬ ፡ ፩ ። ፮ ፡ ዘፍጥ. ፩ ፡ ፳፯ ። ፯ ፡ ዘፍጥ. ፪ ፡ ፳፬ ። ፲፩ ፡ ፲፪ ፡ ማቴ. ፭ ፡ ፴፪ ። ፲፫—፲፮ ፡ ማቴ. ፲፱ ፡ ፲፫—፲፭ ፤ ሉቃ. ፲፰ ፡ ፲፭—፲፯ ። ፲፯—፴፩ ፡ ማቴ. ፲፱ ፡ ፲፮—፴ ፤ ሉቃ. ፲፰ ፡ ፲፰—፴ ።

፲፱ የለም ። ትእዛዛትን ፡ ታውቃለህ ፤ አታመንዝር ፥ አትግደል ፥ አትስረቅ ፥ በሐሰት ፡ አትመስክር ፥ አታታልል ፥ አባትህንና ፡ እናትህን ፡ አክብር ፡ አለው ። ፳ እርሱም ፡ መልሶ ፡— መምህር ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ከሕፃንነቴ ፡ ጀምሬ ፡ ጠብቄአለሁ ፡ አለው ። ፳፩ ኢየሱስም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተመልክቶ ፡ ወደደውና ፡— አንድ ፡ ነገር ፡ ጐደለህ ፤ ሂድ ፥ ያለህን ፡ ሁሉ ፡ሽጠህ ፡ ለድሆች ፡ ስጥ ፥ በሰማ ይም ፡ መዝገብ ፡ታገኛለህ ፥ መስቀሉንም ፡ ተሸ ክመህ ፡ና ፥ ተከተለኝ ፡ አለው ። ፳፪ ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ዚህ ፡ ነገር ፡ ፊቱ ፡ ጠቈረ ፥ ብዙ ፡ ንብረት ፡ ነበረ ውና ፡ እያዘነም ፡ ሄደ ።

፳፫ ኢየሱስም ፡ ዞወር ፡ ብሎ ፡ አይቶ ፡ ደቀ ፡ መዛ ሙርቱን ፡— ገንዘብ ፡ ላላቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአ ብሔር ፡ መንግሥት ፡ መግባት ፡ እንዴት ፡ ጭንቅ ፡ ፳፬ ይሆናል ፡ አላቸው ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ እነዚ ህን ፡ ቃሎች ፡ እደነቁ ። ኢየሱስም ፡ ደግሞ ፡ መልሶ ፡— ልጆች ፡ ሆይ ፥ በገንዘብ ፡ ለሚታመኑ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ መግባት ፡ ፳፭ እንዴት ፡ ጭንቅ ፡ነው ። በለ ፡ ጠጋ ፡ ወደ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ከሚገባ ፡ ግመል ፡ በመ ፳፮ ርፌ ፡ ቀዳዳ ፡ ቢያልፍ ፡ ይቀላል ፡ አላቸው ። እነ ርሱም ፡ ያለ ፡ መጠን ፡ ተገረሙና ፡ እርስ ፡ በር ሳቸው ፡— እንግዲያ ፡ ማን ፡ ሊድን ፡ ይችላል ? ፳፯ ተባባሉ ። ኢየሱስም ፡ ተመለከታቸውና ፡— ይህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ እንጂ ፡ በሰው ፡ ዘንድ ፡ አይቻልም ፤ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ፳፰ ሁሉ ፡ ይቻላልና ፡ አለ ። ጴጥሮስም ፡—እነሆ ፥ እኛ ፡ ሁሉን ፡ ትተን ፡ ተከተልንህ ፡ ይለው ፡ ጀመር ። ፳፱ ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ስለ ፡ እኔና ፡ ስለ ፡ ወንጌል ፡ ቤትን ፡ ወይም ፡ ወንድሞችን ፡ ወይም ፡ እኅቶችን ፡ ወይም ፡ አባትን ፡ ወይም ፡ እናትን ፡ ወይም ፡ ሚስትን ፡ ወይም ፡ ልጆችን ፡ ወይም ፡ እርሻን ፡ ፴ የተወ ፥ አሁን ፡ በዚህ ፡ ዘመን ፡ ከስደት ፡ ጋር ፡ ቤቶችን ፡ ወንድሞችንም ፡ እኅቶችንም ፡ እናቶ ችንም ፡ ልጆችንም ፡ እርሻንም ፡ መቶ ፡ እጥፍ ፥ በሚመጣውም ፡ ዓለም ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ፴፩ የማይቀበል ፡ ማንም ፡ የለም ። ግን ፡ ብዙ ፡ ፊተ ኞች ፡ ኋለኞች ፡ ኋለኞችም ፡ ፊተኞች ፡ ይሆ ናሉ ።

፴፪ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ሊወጡ ፡ በመንገድ ፡ ነበሩ ፥ ኢየሱስም ፡ ይቀድማቸው ፡ ነበርና ፡ ተደ ነቁ ፤ የተከተሉትም ፡ ይፈሩ ፡ ነበር ። ደግሞም ፡ አሥራ ፡ ሁለቱን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አቅርቦ ፡ ይደርስ በት ፡ ዘንድ ፡ ያለውን ፡ ይነግራቸው ፡ ጀመር ፡— ፴፫ እነሆ ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እንወጣለን ፥ የሰው ፡ ልጅም ፡ ለካህናት ፡ አለቆችና ፡ ለጻፎች ፡ አልፎ ፡ ይሰጣል ፥ የሞት ፡ ፍርድም ፡ ይፈርዱበታል ፥ ለአ ሕዛብም ፡ አሳልፈው ፡ ይሰጡታል ፥ ይዘብቱበ ፴፬ ትማል ፡ ይተፉበትማል ፡ ይገርፉትማል ፡ ይገድ ሉትማል ፥ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ይነሣል ፡ አላ ቸው ።

፴፭ የዘብዴዎስ ፡ ልጆች ፡ ያዕቆብና ፡ ዮሐንስም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀርበው ፡— መምህር ፡ ሆይ ፥ የምን ለምንህን ፡ ሁሉ ፡ እንድታደርግልን ፡ እንወዳለን ፡ ፴፮ አሉት ። እርሱም ፡— ምን ፡ ላደርግላችሁ ፡ ትወ ፴፯ ዳላችሁ ? አላቸው ። እነርሱም ፡— በክብርህ ፡ ጊዜ ፡ አንዳችን ፡ በቀኝ ፡ አንዳችንም ፡ በግራህ ፡ ፴፰ መቀመጥን ፡ ስጠን ፡ አሉት ። ኢየሱስ ፡ ግን ፡— የምትለምኑትን ፡ አታውቁም ። እኔ ፡ የምጠጣ ውን ፡ ጽዋ ፡ ልትጠጡ ፥ እኔ ፡ የምጠመቀው ንስ ፡ ጥምቀት ፡ ልትጠመቁ ፡ ትችላላችሁን ? ፴፱ አላቸው ። እነርሱም ፡— እንችላለን ፡ አሉት ። ኢየሱስም ፡— እኔ ፡ የምጠጣውን ፡ ጽዋ ፡ ትጠ ጣላችሁ ፤ እኔ ፡ የምጠመቀውንም ፡ ጥምቀት ፡ ፵ ትጠመቃላችሁ ፤ በቀኝና ፡ በግራ ፡ መቀመጥ ፡ ግን ፡ ለተዘጋጀላቸው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የምሰጥ ፡ ፵፩ እኔ ፡ አይደለሁም ፡ አላቸው ። አሥሩም ፡ ሰም ተው ፡ በያዕቆብና ፡ በዮሐንስ ፡ ይቈጡ ፡ ጀመር ። ፵፪ ኢየሱስም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ጠርቶ ፡ እንዲህ ፡ አላ ቸው ፡— የአሕዛብ ፡ አለቆች ፡ ተብለው ፡ የምታስ ቡት ፡ እንዲገዙአቸው ፡ታላላቆቻቸውም ፡ በላ ፵፫ ያቸው ፡ እንዲሠለጥኑ ፡ ታውቃላችሁ ። በእና ንተስ ፡ እንዲህ ፡ አይደለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ማንም ፡ ከእናንተ ፡ ታላቅ ፡ ሊሆን ፡ የሚወድ ፡ የእናንተ ፡ ፵፬ አገልጋይ ፡ ይሁን ፥ ከእናንተም ፡ ማንም ፡ ፊተኛ ፡ ፵፭ ሊሆን ፡ የሚወድ ፡ የሁሉ ፡ ባሪያ ፡ ይሁን ፤ እን ዲሁ ፡ የሰው ፡ ልጅም ፡ ሊያገለግልና ፡ ነፍሱን ፡ ለብዙዎች ፡ቤዛ ፡ ሊሰጥ ፡ እንጂ ፡ እንዲያገለግ ሉት ፡ አልመጣም ።

፵፮ ወደ ፡ ኢያሪኮም ፡ መጡ ። ከደቀ ፡ መዛሙር ቱና ፡ ከብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ጋር ፡ ከኢያሪኮ ፡ ሲወጣ ፡ የጤሜዎስ ፡ ልጅ ፡ ዕውሩ ፡ በርጤሜዎስ ፡ እየለ ፵፯ መነ ፡ በመንገድ ፡ ዳር ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ። የና ዝሬቱ ፡ ኢየሱስም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡— የዳዊት ፡ ልጅ ፡ ኢየሱስ ፡ ሆይ ፥ ማረኝ ፡ እያለ ፡ ፵፰ ይጮኽ ፡ ጀመር ። ብዙዎችም ፡ ዝም ፡ እንዲል ፡ ገሠጹት ፤ እርሱ ፡ ግን ፡— የዳዊት ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ፵፱ ማረኝ ፡ እያለ ፡ አብዝቶ ፡ ጮኸ ። ኢየሱስም ፡ ቆመና ፡— ጥሩት ፡ አለ ። ዕውሩንም ፡— አይ ፶ ዞህ ፥ ተነሣ ፥ ይጠራሃል ፡ ብለው ፡ ጠሩት ። እር ሱም ፡ እየዘለለ ፡ ተነሥና ፡ ልብሱን ፡ ጥሎ ፡ ወደ ፡ ፶፩ ኢየሱስ ፡ መጣ ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡— ምን ፡ ላደርግልህ ፡ ትወዳለህ ? አለው ። ዕውሩም ፡— ፶፪ መምህር ፡ ሆይ ፥ እይ ፡ ዘንድ ፡ አለው ። ኢየሱ ስም ፡— ሂድ ፤ እምነትህ ፡ አድኖሃል ፡ አለው ። ወዲያውም ፡ አየ ፡ በመንገድም ፡ ተከተለው ።

፲ ። ፲፱ ፤ ዘፀአ. ፳ ፥ ፲፪—፲፯ ። ፴፩ ፤ ማቴ. ፲፱ ፥ ፴ ፣ ሉቃ. ፲፫ ፥ ፴ ። ፴፪—፴፬ ፤ ማቴ. ፳ ፥ ፲፯—፲፱ ፣ ሉቃ. ፲፰ ፥ ፴፩—፴፫ ። ፴፰ ፤ ም. ፲፬ ፥ ፴፮ ። ፵፪—፵፭ ፤ ማቴ. ፳ ፥ ፳—፳፰ ። ፵፫ ፤ ም. ፱ ፥ ፴፭ ፣ ማቴ. ፳፫ ፥ ፲፩ ፣ ሉቃ. ፳፪ ፥ ፳፮ ፣ ፲፱ ፥ ፱ ። ፵፬ ፤ የሐዋ. ፲፱ ፥ ፱ ። ፵፬—፵፭ ፤ ሉቃ. ፳፪ ፥ ፳፭—፳፯ ። ፵፭ ፤ ም. ፱ ፥ ፴፭ ። ፵፮—፶፪ ፤ ማቴ. ፳ ፥ ፳፱—፴፬ ፣ ሉቃ. ፲፰ ፥ ፴፭—፵፫ ። ፶፪ ፤ ም. ፭ ፥ ፴፬ ፣ ማቴ. ፱ ፥ ፳፪ ፣ ሉቃ. ፯ ፥ ፶ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ከደብረ ፡ ዘይት ፡ አጠገብ ፡ ወዳሉቱ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ፋጌና ፡ ወደ ፡ ቢታንያ ፡ በቀረቡ ፡ ጊዜ ፥ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ፪ ሁለቱን ፡ ልኮ ፡— በፊታችሁ ፡ ወዳለችው ፡ መንደር ፡ ሂዱ ፥ ወዲያውም ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ገብታችሁ ፡ ከሰው ፡ ማንም ፡ ገና ፡ ያልተቀመጠበት ፥ ውርንጫ ፡ ታስሮ ፡ ታገኛላችሁ ፤ ፈትታችሁ ፡ ፫ አምጡልኝ ። ማንም ፡— ስለ ፡ ምን ፡ እንዲህ ፡ ታደርጋላችሁ ? ቢላችሁ ፡— ለጌታ ፡ ያስፈልገዋል ፡ በሉት ፥ ወዲያውም ፡ ደግሞ ፡ ወደዚህ ፡ ፬ ይሰደዋል ፡ አላቸው ። ሄዱም ፡ ውርንጫውንም ፡ በመንገድ ፡ መተላለፊያ ፡ በደጅ ፡ ውጭ ፡ ታስሮ ፡ ፭ አገኙት ፥ ፈቱትም ። በዚያም ፡ ከቆሙት ፡ እንዳንዶቹ ፡— ውርንጫውን ፡ የምትፈቱት ፡ ምን ፡ ፮ ልታደርጉት ፡ ነው ? አሉአቸው ። እነርሱም ፡ ኢየሱስ ፡ እንዳዘዘ ፡ አሉአቸው ፤ ተዉአቸ ፯ ውም ። ውርንጫውንም ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡ አመጡት ፥ ልብሳቸውንም ፡ በላዩ ፡ ጣሉ ፥ ተቀመጠ ፰ በትም ። ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ልብሳቸውን ፡ በመንገድ ፡ ላይ ፡ አነጠፉ ፥ ሌሎችም ፡ ከዛፍ ፡ ቅጠ ፱ ሎችን ፡ እየቈረጡ ፡ ያነጥፉ ፡ ነበር ። የሚቀድሙትም ፡ የሚከተሉትም ፡— ሆሣዕና ፤ በጌታ ፡ ፲ ስም ፡ የሚመጣ ፡ የተባረከ ፡ ነው ፤ በጌታ ፡ ስም ፡ የምትመጣ ፡ የአባታችን ፡ የዳዊት ፡ መንግሥት ፡ የተባረከች ፡ ናት ፤ ሆሣዕና ፡ በአርያም ፡ እያሉ ፡ ይጮኹ ፡ ነበር ።

፲፩ ኢየሱስም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ ገባ ፤ ዘወር ፡ ብሎም ፡ ሁሉን ፡ ከተመለከተ ፡ በኋላ ፥ ጊዜው ፡ መሽቶ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ከአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ቢታንያ ፡ ወጣ ።

፲፪ በማግሥቱም ፡ ከቢታንያ ፡ ሲወጡ ፡ ተራበ ። ፲፫ ቅጠልም ፡ ያላት ፡ በለስ ፡ ከሩቅ ፡ አይቶ ፡ ምናልባት ፡ እንዳች ፡ ይገኝበት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ብሎ ፡ መጣ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የበለስ ፡ ወራት ፡ አልነበረምና ፡ መጥቶ ፡ ከቅጠል ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ አላገኘባትም ። ፲፬ መልሶም ፡— ከእሁን ፡ ጀምሮ ፡ ለዘላለም ፡ ማንም ፡ ከአንቺ ፡ ፍሬ ፡ አይብላ ፡ አላት ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ሰሙ ።

፲፭ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ መጡ ። ወደ ፡ መቅደስም ፡ ገብቶ ፡ በመቅደስ ፡ የሚሸጡትንና ፡ የሚገዙትን ፡ ያወጣ ፡ ጀመር ፥ የገንዘብ ፡ ለዋጮችንም ፡ ገበታዎች ፡ የርግብ ፡ ሻጭዎችንም ፡ ወን ፲፮ በሮች ፡ ገለበጠ ፤ ዕቃም ፡ ተሸክሞ ፡ ማንም ፡ በመ ፲፯ ቅደስ ፡ ሊያልፍ ፡ አልፈቀደም ። አስተማራቸውም ፡— ቤቴ ፡ ለአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ የጸሎት ፡ ቤት ፡ ትባላለች ፡ ተብሎ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? እናንተ ፡ ግን ፡ የወንበዶች ፡ ዋሻ ፡ አደረጋችኋት ፡ ፲፰ አላቸው ። የካህናት ፡ አለቆችም ፡ ጻፎችም ፡ ሰምተው ፥ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ በትምህርቱ ፡ ይገረሙ ፡ ስለ ፡ ነበር ፡ ይፈሩት ፡ ነበርና ፡ እንዴት ፡ አድርገው ፡ እንዲያጠፉት ፡ ፈለጉ ። ፲፱ ማታ ፡ ማታም ፡ ከከተማ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ይወጣ ፡ ነበር ።

፳ ማለዳም ፡ ሲያልፉ ፡ በለሲቱን ፡ ከሥርዋ ፡ ፳፩ ደርቃ ፡ አዩአት ። ጴጥሮስም ፡ ትዝ ፡ ብሎት ፡— መምህር ፡ ሆይ ፥ እነሆ ፥ የረገምሃት ፡ በለስ ፡ ደርቃ ፳፪ ለች ፡ አለው ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አላ ፳፫ ቸው ፡— በእግዚአብሔር ፡ እመኑ ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ማንም ፡ ያለው ፡ ነገር ፡ እንዲደረግለት ፡ ቢያምን ፡ በልቡ ፡ ሳይጠራጠር ፥ ይህን ፡ ተራራ ፡— ተነቅለህ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ተወርወር ፡ ፳፬ ቢል ፡ ይሆንለታል ። ስለዚህ ፡ እላችኋለሁ ፥ የጸለያችሁትን ፡ የለመናችሁትንም ፡ ሁሉ ፡ እንዳገ ፳፭ ኛችሁት ፡ እመኑ ፥ ይሆንላችሁማል ። ለጸሎትም ፡ በቆማችሁ ፡ ጊዜ ፥ በሰማያት ፡ ያለው ፡ አባታችሁ ፡ ደግሞ ፡ ኃጢአታችሁን ፡ ይቅር ፡ እንዲላችሁ ፥ በማንም ፡ ላይ ፡ እንዳች ፡ ቢኖርባችሁ ፡ ፳፮ ይቅር ፡ በሉት ። እናንተ ፡ ግን ፡ ይቅር ፡ ባትሉ ፡ በሰማያት ፡ ያለው ፡ አባታችሁም ፡ ኃጢአታችሁን ፡ ይቅር ፡ አይላችሁም ።

፳፯ ደግሞም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጡ ። እርሱም ፡ በመቅደስ ፡ ሲመላለስ ፥ የካህናት ፡ አለቆችና ፡ ጻፎች ፡ ሽማግሌዎችም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጥ ፳፰ ተው ፡— እነዚህን ፡ በምን ፡ ሥልጣን ፡ ታደርጋለህ ? ወይስ ፡ እነዚህን ፡ ለማድረግ ፡ ይህን ፡ ሥልጣን ፡ ማን ፡ ሰጠህ ? አሉት ። ፳፱ ኢየሱስም ፡— እኔም ፡ አንዲት ፡ ነገር ፡ እጠይቃችኋለሁ ፥ እናንተም ፡ መልሱልኝ ፥ እኔም ፡ በምን ፡ ሥልጣን ፡ እነዚህን ፡ እንዳደርግ ፡ እነግራችኋለሁ ። ፴ የዮሐንስ ፡ ጥምቀት ፡ ከሰማይ ፡ ነበረችን ፡ ወይስ ፡ ከሰው ? ፴፩ መልሱልኝ ፡ አላቸው ። እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ ሲነጋገሩ ፡— ከሰማይ ፡ ነው ፡ ብንል ፡— እንግዲያውስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አላመናችሁበትም ? ይለናል ፤ ፴፪ ነገር ፡ ግን ፡— ከሰው ፡ ነው ፡ እንበልን ? አሉ ፤ ሁሉ ፡ ዮሐንስን ፡ በእውነት ፡ እንደ ፡ ነቢይ ፡ ፴፫ ያዩት ፡ ነበርና ፡ ሕዝቡን ፡ ፈሩ ። ለኢየሱስም ፡ መልሰው ፡— አናውቅም ፡ አሉት ። ኢየሱስም ፡— እኔም ፡ በምን ፡ ሥልጣን ፡ እነዚህን ፡ እንዳደርግ ፡ አልነግራችሁም ፡ አላቸው ።

ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ በምሳሌም ፡ ይነግራቸው ፡ ጀመር ። አንድ ፡ ሰው ፡ የወይን ፡ አትክልት ፡ ተከለ ፥ ቅጥርም ፡ ቀጠረለት ፥ መጥመቂያም ፡ ማሰለት ፥ ግንብም ፡ ሠራና ፡ ለገበሬዎች ፡ አከራይቶ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ፪ አገር ፡ ሄደ ። በጊዜውም ፡ ከወይን ፡ አትክልት ፡

፲፩። ፩—፲ ፤ ማቴ. ፳፩ ፥ ፩—፲ ፤ ሉቃ. ፲፱ ፥ ፳፱—፴፰ ፤ ዮሐ. ፲፪ ፥ ፲፪—፲፭ ። ፱ ፤ መዝ. ፻፲፰ ፥ ፳፭ ፡ ፳፮ ። ፲፪—፲፬ ፤ ማቴ. ፳፩ ፥ ፲፰ ፡ ፲፱ ። ፲፭—፲፰ ፤ ማቴ. ፳፩ ፥ ፲፪ ፡ ፲፫ ፤ ሉቃ. ፲፱ ፥ ፵፭ ፡ ፵፮ ፤ ዮሐ. ፪ ፥ ፲፫—፲፯ ። ፲፯ ፤ ኢሳ. ፶፮ ፥ ፯ ፤ ኤር. ፯ ፥ ፲፩ ። ፲፰ ፤ ሉቃ. ፲፱ ፥ ፵፯ ፡ ፵፰ ። ፲፱ ፤ ማቴ. ፳፩ ፥ ፲፯ ። ፳—፳፬ ፤ ማቴ. ፳፩ ፥ ፲፱—፳፪ ። ፳፪ ፤ ዮሐ. ፲፬ ፥ ፩ ። ፳፫ ፤ ማቴ. ፲፯ ፥ ፳ ። ፳፬ ፤ ማቴ. ፯ ፥ ፯ ፤ ሉቃ. ፲፩ ፥ ፱—፲፫ ፤ ዮሐ. ፲፬ ፥ ፲፫ ። ፳፭ ፡ ፳፮ ፤ ማቴ. ፮ ፥ ፲፬ ፡ ፲፭ ። ፳፯—፴፫ ፤ ማቴ. ፳፩ ፥ ፳፫—፳፯ ፤ ሉቃ. ፳ ፥ ፩—፰ ። ፴፪ ፤ ማቴ. ፲፬ ፥ ፭ ።

፲፪። ፩—፲፪ ፤ ማቴ. ፳፩ ፥ ፴፫—፵፮ ፤ ሉቃ. ፳ ፥ ፱—፲፱ ፤ ኢሳ. ፭ ፥ ፩ ፡ ፪ ።

ፍሬ ፡ ከገበሬዎቹ ፡ እንዲቀበል ፡ አንድ ፡ ባሪያ ፡
፫ ወደ ፡ ገበሬዎቹ ፡ ላከ ፤ ይዘውም ፡ ደበደቡት ፡
፬ ባዶውንም ፡ ሰደዱት ። ዳግመኛም ፡ ሌላውን ፡
ባሪያ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ላከ ፡ እርሱንም ፡ ወግረው ፡
ራሱን ፡ አቈሰሉት ፡ አዋርደውም ፡ ሰደዱት ።
፭ ሌላውንም ፡ ላከ ፤ እርሱንም ፡ ገደሉት ፤ ከሌሎ
ችም ፡ ከብዙዎች ፡ አንዳንዱን ፡ ደበደቡ ፡ አን
፮ ዳንዱንም ፡ ገደሉ ። የሚወደው ፡ አንድ ፡ ልጅ ፡
ግን ፡ ነበረው ፤ ልጄንስ ፡ ያፍሩታል ፡ ብሎ ፡ እር
፯ ሱን ፡ ከሁሉ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ላከ ። እነ
ዚያ ፡ ገበሬዎች ፡ ግን ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፦
ወራሹ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ኑ ፥ እንግደለው ፥ ርስቱም ፡
፰ ለኛ ፡ ይሆናል ፡ ተባባሉ ። ይዘውም ፡ ገደሉት ፥
ከወይኑም ፡ አትክልት ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ጣሉት ።
፱ እንግዲህ ፡ የወይኑ ፡ አትክልት ፡ ጌታ ፡ ምን ፡ ያደ
ርጋል ? ይመጣል ፡ ገበሬዎቹንም ፡ ያጠፋል ፥
የወይኑንም ፡ አትክልት ፡ ለሌሎች ፡ ይሰጣል ።

፲፡፲፩ ግንበኞች ፡ የናቁት ፡ ድንጋይ ፡ እርሱ ፡ የማ
ዕዘን ፡ ራስ ፡ ሆነ ፤ ይህም ፡ ከጌታ ፡ ዘንድ ፡
ሆነ ፥ ለዓይናችንም ፡ ድንቅ ፡ ነው ፡

የሚለውን ፡ ይህን ፡ መጽሐፍ ፡ አላነበባችሁምን ?
፲፪ ምሳሌውንም ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡
አውቀዋልና ፡ ሊይዙት ፡ ፈለጉ ፥ ነገር ፡ ግን ፡
ሕዝቡን ፡ ፈሩ ። ትተውትም ፡ ሄዱ ።

፲፫ በንግግርም ፡ ሊያጠምዱት ፡ ከፈሪሳውያንና ፡
ከሄሮድስ ፡ ወገን ፡ የሆኑትን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ላኩ ።
፲፬ መጥተውም ፦ መምህር ፡ ሆይ ፥ የሰውን ፡ ፊት ፡
ሳትመለከት ፡ በእውነት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መን
ገድ ፡ ታስተምራለህና ፡ እውነተኛ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡
ለማንምም ፡ እንዳታደላ ፡ እናውቃለን ፤ ለቄሣር ፡
ግብር ፡ መስጠት ፡ ተፈቅዶአልን ፡ ወይስ ፡ አልተ
ፈቀደም ? እንስጥን ፡ ወይስ ፡ አንስጥ ? አሉት ።
፲፭ እርሱ ፡ ግን ፡ ግብዝነታቸውን ፡ አውቆ ፦ ስለ ምን ፡
ትፈትኑኛላችሁ ? አየው ፡ ዘንድ ፡ አንድ ፡ ዲናር ፡
፲፮ አምጡልኝ ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡ አመጡ
ለት ። ይህች ፡ መልክ ፡ ጽሕፈቱስ ፡ የማን ፡
ናት ? አላቸው ፤ እነርሱም ፦ የቄሣር ፡ ናት ፡
፲፯ አሉት ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፦ የቄሣርን ፡ ለቄ
ሣር ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡
አስረክቡ ፡ አላቸው ። በርሱም ፡ ተደነቁ ።

፲፰ ትንሣኤ ፡ ሙታን ፡ የለም ፡ የሚሉ ፡ ሰዱቃ
ውያን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጥተው ፡ ጠየቁት ፡ እን
፲፱ ዲህም ፡ አሉት ፦ መምህር ፡ ሆይ ፥ ሙሴ ፦
የአንድ ፡ ሰው ፡ ወንድም ፡ ሚስቱን ፡ ትቶ ፡ ልጅ ፡
ሳያስቀር ፡ ቢሞት ፥ ወንድሙ ፡ ሚስቱን ፡ አግ
ብቶ ፡ ለወንድሙ ፡ ዘር ፡ ይተካ ፡ ብሎ ፡ ጻፈልን ።
፳ ሰባት ፡ ወንድማማቾች ፡ ነበሩ ፤ ፊተኛውም ፡
፳፩ ሚስት ፡ አግብቶ ፡ ዘር ፡ ሳያስቀር ፡ ሞተ ፤ ሁለተ
ኛውም ፡ አገባት ፥ ዘርም ፡ ሳይተው ፡ ሞተ ፤ ሦስ
፳፪ ተኛውም ፡ እንዲሁ ፤ ሰባቱም ፡ አገቡአት ፥ ዘርም ፡
አላስቀሩም ። ከሁሉም ፡ በኋላ ፡ ሴቲቱ ፡ ደግሞ ፡
፳፫ ሞተች ። ሰባቱ ፡ አግብተዋታልና ፡ በትንሣኤ ፡
ቀን ፡ ሲነሡ ፡ ከእነርሱ ፡ ለማናቸው ፡ ሚስት ፡
ትሆናለች ?

፳፬ ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦
መጻሕፍትንና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ኃይል ፡ አታ
ውቁምና ፡ ስለዚህ ፡ የምትስቱ ፡ አይደለምን ?
፳፭ ከሙታንስ ፡ ሲነሡ ፡ በሰማያት ፡ እንዳሉ ፡ መላ
እክት ፡ ይሆናሉ ፡ እንጂ ፡ አያገቡም ፥ አይጋቡ
፳፮ ምም ። ስለ ፡ ሙታን ፡ ግን ፡ እንዲነሡ ፡ እግዚ
አብሔር ፦

እኔ ፡ የአብርሃም ፡ አምላክ ፡ የይስሐቅም ፡
አምላክ ፡ የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ ነኝ ፡

እንዳለው ፡ በሙሴ ፡ መጽሐፍ ፡ በቍጥቋጦው ፡
፳፯ ዘንድ ፡ የተጻፈውን ፡ አላነበባችሁምን ? የሕያ
ዋን ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የሙታን ፡ አይደ
ለም ። እንግዲህ ፡ እጅግ ፡ ትስታላችሁ ።

፳፰ ከጻፎችም ፡ አንዱ ፡ ቀርቦ ፡ ሲከራከሩ ፡ ሰማና ፡
መልካም ፡ አድርጎ ፡ እንደ ፡ መለሰላቸው ፡ አስተ
ውሎ ፦ ከሁሉ ፡ ፊተኛይቱ ፡ ትእዛዝ ፡ ማናቸ
፳፱ ይቱ ፡ ናት ? ብሎ ፡ ጠየቀው ። ኢየሱስም ፡
መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፦ ከትእዛዛቱ ፡ ሁሉ ፡
ፊተኛይቱ ፦ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ ስማ ፤ ጌታ ፡
፴ አምላካችን ፡ አንድ ፡ ጌታ ፡ ነው ፥ አንተም ፡ በፍ
ጹም ፡ ልብህ ፡ በፍጹምም ፡ ነፍስህ ፡ በፍጹምም ፡
አሳብህ ፡ በፍጹምም ፡ ኃይልህ ፡ ጌታ ፡ አምላክ
ህን ፡ ውደድ ፡ የምትል ፡ ናት ። ፊተኛይቱ ፡ ትእ
፴፩ ዛዝ ፡ ይህች ፡ ናት ። ሁለተኛይቱም ፦ ባልንጀ
ራህን ፡ እንደ ፡ ራስህ ፡ ውደድ ፡ የምትል ፡ እርስ
ዋን ፡ የምትመስል ፡ ይህች ፡ ናት ። ከእነዚህ ፡
፴፪ የምትበልጥ ፡ ሌላ ፡ ትእዛዝ ፡ የለችም ። ጻፊ
ውም ፦ መልካም ፡ ነው ፥ መምህር ፡ ሆይ ፤
አንድ ፡ ነው ፡ ከእርሱም ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ የለም ፡
፴፫ ብለህ ፡ በእውነት ፡ ተናገርህ ፤ በፍጹም ፡ ልብ ፡
በፍጹም ፡ አእምሮም ፡ በፍጹም ፡ ነፍስም ፡ በፍ
ጹም ፡ ኃይልም ፡ እርሱን ፡ መውደድ ፥ ባልንጀ
ራንም ፡ እንደ ፡ ራስ ፡ መውደድ ፡ በሙሉ ፡ ከሚ
ቃጠል ፡ መሥዋዕትና ፡ ከሌላው ፡ መሥዋዕት ፡
፴፬ ሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ ነው ፡ አለው ። ኢየሱስም ፡
በአእምሮ ፡ እንደ ፡ መለሰ ፡ አይቶ ፦ አንተ ፡ ከእ
ግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ የራቅህ ፡ አይደለ
ህም ፡ አለው ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ማንም ፡ ሊጠ
ይቀው ፡ አልደፈረም ።

፴፭ ኢየሱስም ፡ በመቅደስ ፡ ሲያስተምር ፡ መልሶ ፡
እንዲህ ፡ አለ ፦ ጻፎች ፡ ክርስቶስ ፡ የዳዊት ፡
፴፮ ልጅ ፡ ነው ፡ እንዴት ፡ ይላሉ ? ዳዊት ፡ ራሱ ፡
በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፦

ጌታ ፡ ጌታዬን ፦ ጠላቶችህን ፡ የእግርህ ፡
መረገጫ ፡ እስካደርግልህ ፡ ድረስ ፡ በቀኜ ፡
ተቀመጥ ፡ አለው ፡

፲፪ ። ፲ ፡ ፲፩ ፡ መዝ. ፻፲፰ ፡ ፳፪ ፡ ፳፫ ። ፲፯ ፡ ሮሜ. ፲፫ ፡ ፯ ። ፲፰—፳፯ ፡ ማቴ. ፳፪ ፡ ፳፫—፴፫ ፤ ሉቃ. ፳ ፡ ፳፯—፴፰ ።
፲፱ ፡ ዘዳግ. ፳፭ ፡ ፭ ። ፳፮ ፡ ዘጸ. ፫ ፡ ፮ ። ፳፰—፴፬ ፡ ማቴ. ፳፪ ፡ ፴፬—፵ ፤ ሉቃ. ፲ ፡ ፳፭—፳፰ ፤ ፳ ፡ ፴፱ ፡ ፵ ።
፳፱ ፡ ፴ ፡ ዘዳግ. ፮ ፡ ፬ ፡ ፭ ። ፴፩ ፡ ዘሌዋ. ፲፱ ፡ ፲፰ ። ፴፫ ፡ ፩ ሳሙ. ፲፭ ፡ ፳፪ ። ፴፭—፴፯ ፡ ማቴ. ፳፪ ፡ ፵፩—፵፮ ፤
ሉቃ. ፳ ፡ ፵፩—፵፬ ። ፴፮ ፡ መዝ. ፻፲ ፡ ፩ ።

፴፯፤ አለ ። ዳዊት ፡ ራሱ ፡ ጌታ ፡ አለው ፤ እንዴት ፡ ልጁ ፡ ይሆናል ? ብዙ ፡ ሕዝብም ፡ በደስታ ፡ ይሰሙት ፡ ነበር ።

፴፰፡፴፱፤ ሲያስተምርም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ረጃጅም ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡ መዞርን ÷ በገበያም ፡ ሰላምታን ÷ በምኵራብም ፡ የከበሬታን ፡ ወንበር ÷ በግብርም ፡ የከበሬታን ፡ ስፍራ ፡ ከሚወዱ ፡ ከጻፎች ፡
፵፤ ተጠበቁ ፤ የመበለቶችን ፡ ቤት ፡ የሚበሉ ፡ ጸሎታቸውንም ፡ በማስረዘም ፡ የሚያመካኙ ፡ እነዚህ ፡ የባሰ ፡ ፍርድ ፡ ይቀበላሉ ።

፵፩፤ ኢየሱስም ፡ በመዝገብ ፡ አንጻር ፡ ተቀምጦ ፡ ሕዝቡ ፡ በመዝገቡ ፡ ውስጥ ፡ ገንዘብ ፡ እንዴት ፡ እንዲጥሉ ፡ ያይ ፡ ነበር ፤ ብዙ ፡ ባለ ፡ ጠጎችም ፡
፵፪፤ ብዙ ፡ ይጥሉ ፡ ነበር ፤ አንዲትም ፡ ድሀ ፡ መበለት ፡ መጥታ ፡ አንድ ፡ ሳንቲም ፡ የሚያህሉ ፡ ሁለት ፡
፵፫፤ ናስ ፡ ጣለች ። ደቀ ፡ መዛሙርቱንም ፡ ጠርቶ ፡— እውነት ፡ እላችኋለሁ ÷ በመዝገብ ፡ ውስጥ ፡ ከሚጥሉት ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ይህች ፡ ድሀ ፡ መበለት ፡
፵፬፤ አብልጣ ፡ ጣለች ፤ ሁሉ ፡ ከትርፋቸው ፡ጥለዋልና ÷ ይህች ፡ ግን ፡ ከጕድለትዋ ፡ የነበራትን ፡ ሁሉ ፡ ትዳርዋን ፡ ሁሉ ፡ ጣለች ፡ አላቸው ።

ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩፤ እርሱም ፡ ከመቅደስ ፡ ሲወጣ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ አንዱ ፡— መምህር ፡ ሆይ ÷ እንዴት ፡ ያሉ ፡ ድንጋይዎችና ፡ እንዴት ፡ ያሉ ፡ ሕንጻዎች ፡ እንደ ፡
፪፤ ሆኑ ፡ እይ ፡ አለው ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡— እነዚህን ፡ ታላላቅ ፡ ሕንጻዎች ፡ ታያለህን ? ድንጋይ ፡ በድንጋይ ፡ ላይ ፡ ሳይፈርስ ፡ በዚህ ፡ አይቀርም ፡ አለው ።

፫፤ በመቅደስም ፡ ትይዩ ፡ በደብረ ፡ ዘይት ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ÷ ጴጥሮስና ፡ ያዕቆብ ፡ ዮሐንስም ፡
፬፤ እንድርያስም ፡— ንገረን ÷ ይህ ፡ መቼ ፡ ይሆናል ? ይህስ ፡ ሁሉ ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ እንዳለው ፡ ምልክቱ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብለው ፡ ለብቻቸው ፡
፭፤ ጠየቁት ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ ይላቸው ፡ ጀመር ፡— ማንም ፡ እንዳያስታችሁ ፡ ተጠ
፮፤ ንቀቁ ። ብዙዎች ፡— እኔ ፡ ነኝ ፡ እያሉ ፡ በስሜ ፡
፯፤ ይመጣሉና ÷ ብዙዎችንም ፡ ያስታሉ ። ጦርንም ፡ የጦርንም ፡ ወሬ ፡ በሰማችሁ ፡ ጊዜ ፡ አትደንግጡ ፤ ይህ ፡ ሊሆን ፡ ግድ ፡ ነውና ÷ ነገር ፡
፰፤ ግን ፡ መጨረሻው ፡ ገና ፡ ነው ። ሕዝብ ፡ በሕዝብ ፡ ላይ ፡ መንግሥትም ፡ በመንግሥት ፡ ላይ ፡ ይነሣልና ፤ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ስፍራ ፡ የምድር ፡ መናወጥ ፡ ይሆናል ፤ ራብ ፡ ይሆናል ፤ እነዚህ ፡ የምጥ ፡ ጣር ፡ መጀመሪያ ፡ ናቸው ።

፱፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ለራሳችሁ ፡ ተጠንቀቁ ፤ ወደ ፡ ሸንጎ ፡ አሳልፈው ፡ ይሰጡአችኋል ፡ በምኵራብም ፡ ትገረፋላችሁ ፡ ምስክርም ፡ ይሆንባቸው ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ በገዥዎችና ፡ በነገሥታት ፡
፲፤ ፊት ፡ ትቆማላችሁ ። አስቀድሞም ፡ ወንጌል ፡ ለአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ይሰበክ ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ።
፲፩፤ ሲጐትቱአችሁና ፡ አሳልፈው ፡ ሲሰጡአችሁም ፡ ምን ፡ እንድትናገሩ ፡ አስቀድማችሁ ፡ አትጨነቁ ÷ ዳሩ ፡ ግን ፡ በዚያች ፡ ሰዓት ፡ የሚሰጣችሁን ፡ ተናገሩ ፤ የሚነግረው ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡
፲፪፤ ነው ፡ እንጂ ፡ እናንተ ፡ አይደላችሁምና ። ወንድምም ፡ ወንድሙን ፡ አባትም ፡ ልጁን ፡ ለሞት ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣል ÷ ልጆችም ፡ በወላጆቻቸው ፡
፲፫፤ ላይ ፡ ይነሣሉ ፡ ይገድሉአቸውማል ፤ በሁሉም ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ስሜ ፡ የተጠላችሁ ፡ ትሆናላችሁ ፤ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ የሚጸና ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ ይድናል ።

፲፬፤ ነገር ፡ ግን ፡ በነቢዩ ፡ በዳንኤል ፡ የተባለውን ፡ የጥፋት ፡ ርኵሰት ፡ በማይገባው ፡ ስፍራ ፡ ቆሞ ፡ ብታዩ ÷ አንባቢው ፡ ያስተውል ÷ በዚያን ፡ ጊዜ ፡
፲፭፤ በይሁዳ ፡ ያሉ ፡ ወደ ፡ ተራሮች ፡ ይሽሹ ÷ በሰገነትም ፡ ያለ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ አይውረድ ፡ ከቤቱም ፡
፲፮፤ አንዳች ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ፡ አይግባ ÷ በእርሻም ፡ ያለ ፡ ልብሱን ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡
፲፯፤ አይመለስ ። በዚያን ፡ ወራትም ፡ ለርጉዞችና ፡
፲፰፤ ለሚያጠቡ ፡ ወዮላቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ ሽሽታ
፲፱፤ ችሁ ፡ በክረምት ፡ እንዳይሆን ፡ ጸልዩ ፤ በዚያን ፡ ወራት ፡ እግዚአብሔር ፡ ከፈጠረው ፡ ከፍጥረት ፡ መጀመሪያ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ ድረስ ፡ ያልሆነ ፡ ደግሞም ፡ የማይሆን ፡ የመከራ ፡ ዓይነት ፡
፳፤ ይሆናልና ። ጌታስ ፡ ወራቶቹን ፡ ባያሳጥር ÷ ሥጋ ፡ የለበሰ ፡ ሁሉ ፡ ባልዳነም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ መረ
፳፩፤ ጣቸው ፡ ምርጦች ፡ ወራቶቹን ፡ አሳጠረ ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ማንም ፡— እነሆ ÷ ክርስቶስ ፡ ከዚህ ፡ አለ ÷ ወይም ፡— እነሆ ÷ ከዚያ ፡ አለ ፡ ቢላችሁ ፡
፳፪፤ አትመኑ ፤ ሐሰተኞች ፡ ክርስቶሶችና ፡ ሐሰተኞች ፡ ነቢያት ፡ ይነሣሉና ÷ ቢቻላቸውስ ፡ የተመረጡትን ፡ እንኳ ፡ ያስቱ ፡ ዘንድ ፡ ምልክትና ፡
፳፫፤ ድንቅ ፡ ያደርጋሉ ። እናንተ ፡ ግን ፡ ተጠንቀቁ ፤ እነሆ ÷ አስቀድሜ ፡ ሁሉን ፡ ነገርኋችሁ ።

፳፬፤ በዚያን ፡ ወራት ፡ ግን ፡ ከዚያ ፡ መከራ ፡ በኋላ ፡ ፀሐይ ፡ ይጨልማል ፡ ጨረቃም ፡ ብርሃንዋን ፡
፳፭፤ አትሰጥም ÷ ከዋክብትም ፡ ከሰማይ ፡ ይወድቃሉ ÷
፳፮፤ የሰማያትም ፡ ኀይላት ፡ ይናወጣሉ ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በብዙ ፡ ኀይልና ፡ ክብር ፡
፳፯፤ በደመና ፡ ሲመጣ ፡ ያዩታል ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ መላእክትን ፡ ይልካል ፡ ከአራቱ ፡ ነፋሳትም ፡ ከምድር ፡ዳርቻ ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ዳርቻ ፡ የተመረጡትን ፡ ይሰበስባቸዋል ።

፳፰፤ ምሳሌውንም ፡ ከበለስ ፡ ተማሩ ፤ ጫፍዋ ፡ ሲለሰልስ ፡ ቅጠልዋም ፡ ሲያቈጠቍጥ ÷ ያን ፡ ጊዜ ፡
፳፱፤ በጋ ፡ እንደ ፡ ቀረበ ፡ ታውቃላችሁ ፤ እንዲሁ ፡ ደግሞ ፡ እናንተ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ መሆኑን ፡ ስታዩ ፡
፴፤ ቀርቦ ፡ በደጅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እወቁ ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ÷ ይህ ፡ ሁሉ ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡ ይህ ፡
፴፩፤ ትውልድ ፡ አያልፍም ። ሰማይና ፡ ምድር ፡ ያልፋሉ ፡ ቃሌ ፡ ግን ፡ አያልፍም ።

፲፪ ። ፴፰—፵ ፡ ማቴ. ፳፫ ፡ ፭ ፡ ፮ ፡ ፲፬ ፡ ሉቃ. ፳ ፡ ፵፮—፵፯ ። ፵፩—፵፬ ፡ ሉቃ. ፳፩ ፡ ፩—፬ ፡ ፪ ነገሥ. ፲፪ ፡ ፱ ።
፲፫ ። ፩—፴፪ ፡ ማቴ. ፳፬ ፡ ፩—፴፮ ፡ ሉቃ. ፳፩ ፡ ፭—፴፮ ። ፪ ፡ ሉቃ. ፲፱ ፡ ፵፬ ። ፱—፲፫ ፡ ማቴ. ፲ ፡ ፲፯—፳፪ ፡ ሉቃ. ፲፪ ፡ ፲፩ ፡ ፲፪ ። ፲ ፡ ማቴ. ፳፰ ፡ ፲፱ ። ፲፩ ፡ ሉቃ. ፲፪ ፡ ፲፩ ። ፲፬ ፡ ዳን. ፱ ፡ ፳፯ ። ፳፭ ፡ ኢሳ. ፲፫ ፡ ፲ ።

፴፪ ስለዚያች ፡ ቀን ፡ ወይም ፡ ስለዚያች ፡ ሰዓት ፡ ግን ፡ የሰማይ ፡ መላእክትም ፡ ቢሆኑ ፡ ልጅም ፡ ቢሆን ፡ ከአብ ፡ በቀር ፡ የሚያውቅ ፡ የለም ። ፴፫ ጊዜው ፡ መቼ ፡ እንዲሆን ፡ አታውቁምና ፡ ተጠንቀቁ ፤ ትጉ ፤ ጸልዩም ። ፴፬ ቤቱን ፡ ትቶ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ አገር ፡ እንደ ፡ ሄደ ፡ ሰው ፡ ነው ፥ ለባሮቹም ፡ ሥልጣን ፡ ለእያንዳንዱም ፡ ሥራውን ፡ ሰጥቶ ፡ በረኛውን ፡ እንዲተጋ ፡ አዘዘ ። ፴፭ እንግዲህ ፡ በማታ ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ በእኩለ ፡ ሌሊት ፡ ወይም ፡ ዶሮ ፡ ሲጮኽ ፡ ወይም ፡ በማለዳ ፡ ቢሆን ፡ ባለቤቱ ፡ መቼ ፡ እንዲመጣ ፡ አታውቁምና ፡ ፴፮ ድንገት ፡ መጥቶ ፡ ተኝታችሁ ፡ እንዳያገኛችሁ ፡ ስለዚህ ፡ ትጉ ። ፴፯ ለእናንተም ፡ የምነግራችሁን ፡ ለሁሉ ፡ እላለሁ ፤ ትጉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ ከሁለት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ፋሲካና ፡ የቂጣ ፡ በዓል ፡ ነበረ ። የካህናት ፡ አለቆችም ፡ ጻፎችም ፡ እንዴት ፡ አድርገው ፡ በተንኰል ፡ እንደሚይዙትና ፡ ፪ እንደሚገድሉት ፡ ይፈልጉ ፡ ነበር ። የሕዝብ ፡ ሁከት ፡ እንዳይሆን ፡ በበዓል ፡ አይሁን ፡ ይሉ ፡ ነበርና ።

፫ እርሱም ፡ በቢታንያ ፡ በለምጻሙ ፡ በስምዖን ፡ ቤት ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፥ በማዕድ ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፥ አንዲት ፡ ሴት ፡ ዋጋው ፡ እጅግ ፡ የከበረ ፡ ጥሩ ፡ ናርዶስ ፡ ሽቱ ፡ የመላበት ፡ የአልባስጥሮስ ፡ ቢልቃጥ ፡ ይዛ ፡ መጣች ፤ ቢልቃጡንም ፡ ሰብራ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ አፈሰሰችው ። ፬ አንዳንዶችም ፡— ይህ ፡ የሽቱ ፡ ጥፋት ፡ ለምንድር ፡ ነው ? ፭ ይህ ፡ ሽቱ ፡ ከሦስት ፡ መቶ ፡ ዲናር ፡ በሚበልጥ ፡ ዋጋ ፡ ተሽጦ ፡ ለድሆች ፡ ሊሰጥ ፡ ይቻል ፡ ነበርና ፡ ብለው ፡ በራሳቸው ፡ ይቈጡ ፡ ነበር ፤ እርስዋንም ፡ ነቀፉአት ። ፮ ኢየሱስ ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ተዉአት ፤ ስለ ፡ ምን ፡ ታደክሙአታላችሁ ? መልካም ፡ ሥራ ፡ ሠርታልኛለች ። ፯ ድሆች ፡ ሁልጊዜ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይኖራሉና ፥ በማናቸውም ፡ በወደዳችሁት ፡ ጊዜ ፡ መልካም ፡ ልታደርጉላቸው ፡ ትችላላችሁ ፥ እኔ ፡ ግን ፡ ሁልጊዜ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ አልኖርም ። ፰ የተቻላትን ፡ አደረገች ፤ አስቀድማ ፡ ለመቃብሬ ፡ ሥጋዬን ፡ ቀባችው ። ፱ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ይህ ፡ ወንጌል ፡ በዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ በሚሰበክበት ፡ በማናቸውም ፡ ስፍራ ፥ እርስዋ ፡ ያደረገችው ፡ ደግሞ ፡ ለእርስዋ ፡ መታሰቢያ ፡ ሊሆን ፡ ይነገራል ።

፲ ከአሥራ ፡ ሁለቱም ፡ አንዱ ፡ የአስቆሮቱ ፡ ይሁዳ ፡ አሳልፎ ፡ ሊሰጠው ፡ ወደ ፡ ካህናት ፡ አለቆች ፡ ሄደ ። ፲፩ ሲሰሙም ፡ ደስ ፡ አላቸው ፡ ብርም ፡ ይሰጡት ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ ሰጡት ። በሚመች ፡ ጊዜም ፡ እንዴት ፡ አድርጎ ፡ አሳልፎ ፡ እንዲሰጠው ፡ ይፈልግ ፡ ነበር ።

፲፪ ፋሲካን ፡ በሚያርዱበት ፡ በቂጣ ፡ በዓል ፡ መጀመሪያ ፡ ቀን ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡— ፋሲካን ፡ ትበላ ፡ ዘንድ ፡ ወዴት ፡ ሄደን ፡ ልናሰናዳ ፡ ትወዳለህ ? አሉት ። ፲፫ ከደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ሁለት ፡ ላከ ፡ እንዲህም ፡ አላቸው ፡— ወደ ፡ ከተማ ፡ ሂዱ ፥ ማድጋ ፡ ውኃ ፡ የተሸከመ ፡ ሰውም ፡ ይገናኛችኋል ፤ ተከተሉት ፥ ፲፬ የሚገባበትንም ፡ የቤቱን ፡ ጌታ ፡— መምህሩ ፡— ከደቀ ፡ መዛሙርቴ ፡ ጋር ፡ ፋሲካን ፡ የምበላበት ፡ የእንግዳ ፡ ቤት ፡ ወዴት ፡ ነው ? ይላል ፡ በሉት ። ፲፭ እርሱም ፡ በደርብ ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ የተሰናዳና ፡ የተነጠፈ ፡ ታላቅ ፡ አዳራሽ ፡ ያሳያችኋል ፤ በዚያም ፡ አሰናዱልን ። ፲፮ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ወጡ ፡ ወደ ፡ ከተማም ፡ ሄደው ፡ እንዳላቸው ፡ አገኙ ፥ ፋሲካንም ፡ አሰናዱ ።

፲፯ በመሸም ፡ ጊዜ ፡ ከአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ጋር ፡ መጣ ። ፲፰ ተቀምጠውም ፡ ሲበሉ ፡ ኢየሱስ ፡— እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ከእናንተ ፡ አንዱ ፥ እርሱም ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ የሚበላው ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጠኛል ፡ አለ ። ፲፱ እነርሱም ፡ ያዝኑ ፥ እያንዳንዳቸውም ፡— እኔ ፡ እሆንን ? ይሉት ፡ ጀመር ። ፳ እርሱም ፡ መልሶ ፡— ከአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ አንዱ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ወጭቱ ፡ እጁን ፡ የሚያጠልቀው ፡ ነው ። ፳፩ የሰው ፡ ልጅስ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ይሄዳል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ አልፎ ፡ ለሚሰጥበት ፡ ለዚያ ፡ ሰው ፡ ወዮለት ፤ ያ ፡ ሰው ፡ ባልተወለደ ፡ ይሻለው ፡ ነበር ፡ አላቸው ።

፳፪ ሲበሉም ፡ ኢየሱስ ፡ እንጀራን ፡ አንሥቶ ፡ ባረከ ፡ ቈርሶም ፡ ሰጣቸውና ፡— እንኩ ፤ ይህ ፡ ሥጋዬ ፡ ነው ፡ አለ ። ፳፫ ጽዋውንም ፡ አንሥቶ ፡ አመስግኖም ፡ ሰጣቸው ፥ ሁሉም ፡ ከእርሱ ፡ ጠጡ ። ፳፬ እርሱም ፡— ይህ ፡ ስለ ፡ ብዙዎች ፡ የሚፈስ ፡ የአዲስ ፡ ኪዳን ፡ ደሜ ፡ ነው ። ፳፭ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ በእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ከወይኑ ፡ ፍሬ ፡ አዲሱን ፡ እስከምጠጣበት ፡ እስከዚያ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ደግሞ ፡ አልጠጣውም ፡ አላቸው ።

፳፮ መዝሙርም ፡ ከዘመሩ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡ ወጡ ። ፳፯ ኢየሱስም ፡— በዚች ፡ ሌሊት ፡ ሁላችሁ ፡ በእኔ ፡ ትሰናከላላችሁ ፤ እረኛውን ፡ እመታለሁ ፡ በጎችም ፡ ይበተናሉ ፡ የሚል ፡ ተጽፎአልና ። ፳፰ ነገር ፡ ግን ፡ ከተነሣሁ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ እቀድማችኋለሁ ፡ አላቸው ። ፳፱ ጴጥሮስም ፡— ሁሉም ፡ ቢሰናከሉ ፡ እኔ ፡ ግን ፡ ከቶ ፡ አልሰናከልም ፡ አለው ። ፴ ኢየሱስም ፡— እውነት ፡ እልሃለሁ ፥ ዛሬ ፡ በዚች ፡ ሌሊት ፡ ዶሮ ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ሳይጮኽ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ትክደኛለህ ፡ አለው ። ፴፩ እርሱም ፡ ታላቅ ፡ አበርትቶ ፡— ከአንተ ፡ ጋር ፡ የምሞት ፡ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ ከቶ ፡

፲፫ ። ፴፫ ፤ ሉቃ ፡ ፲፪ ፥ ፵፰ ።
፲፬ ። ፩—፪ ፤ ማቴ ፡ ፳፮ ፥ ፪—፭ ፤ ሉቃ ፡ ፳፪ ፥ ፩፡፪ ። ፫—፱ ፤ ማቴ ፡ ፳፮ ፥ ፮—፲፫ ፤ ሉቃ ፡ ፯ ፥ ፴፯፡፴፰ ፤ ዮሐ ፡ ፲፪ ፥ ፩—፰ ። ፯ ፤ ዘዳግ ፡ ፲፭ ፥ ፲፩ ። ፲—፲፩ ፤ ማቴ ፡ ፳፮ ፥ ፲፬—፲፮ ፤ ሉቃ ፡ ፳፪ ፥ ፫—፮ ። ፲፪—፳፩ ፤ ማቴ ፡ ፳፮ ፥ ፲፯—፳፭ ፤ ሉቃ ፡ ፳፪ ፥ ፯—፲፬ ፡ ፳፩—፳፫ ፤ ዮሐ ፡ ፲፫ ፥ ፳፩—፴ ። ፳፪—፳፭ ፤ ማቴ ፡ ፳፮ ፥ ፳፮—፳፱ ፤ ሉቃ ፡ ፳፪ ፥ ፲፭—፳ ፤ ፩ ቆሮ ፡ ፲፩ ፥ ፳፫—፳፭ ። ፳፮—፴፩ ፤ ማቴ ፡ ፳፮ ፥ ፴—፴፭ ። ፳፯ ፤ ዘካ ፡ ፲፫ ፥ ፯ ። ፴ ፤ ሉቃ ፡ ፳፪ ፥ ፴፬ ፤ ዮሐ ፡ ፲፫ ፥ ፴፰ ።

አልክድህም ፡ አለ ፡፡ ሁሉም ፡ ደግሞ ፡ እንደ ዚሁ ፡ አሉ ፡፡

፴፪ ጌቴሴማኒ ፡ ወደምትባልም ፡ ስፍራ ፡ መጡ ፤ ደቀ ፡ መዛሙርቱንም ፦ ስጸልይ ፡ ሳለሁ ፡ በዚህ ፡ ተቀመጡ ፡ አላቸው ፡፡ ፴፫ ጴጥሮስንና ፡ ያዕቆብን ፡ ዮሐንስንም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ወሰደ ፤ ሊደነግጥም ፡ ሊተክዝም ፡ ጀመረ ፡፡ ፴፬ ነፍሴ ፡ እስከ ፡ ሞት ፡ ድረስ ፡ እጅግ ፡ አዘነች ፤ በዚህ ፡ ቈዩ ፡ ትጉም ፡ አላቸው ፡፡ ፴፭ ጥቂትም ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ በምድርም ፡ ወድቆ ፤ ይቻልስ ፡ ቢሆን ፡ ሰዓቲቱ ፡ ከእርሱ ፡ እንድታልፍ ፡ ጸለየና ፦ ፴፮ አባ ፡ አባት ፡ ሆይ ፤ ሁሉ ፡ ይቻልሃል ፤ ይህችን ፡ ጽዋ ፡ ከእኔ ፡ ውሰድ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አንተ ፡ የምትወደው ፡ እንጂ ፡ እኔ ፡ የምወደው ፡ አይሁን ፡ አለ ፡፡ ፴፯ መጥቶም ፡ ተኝተውም ፡ አገኛቸው ፤ ጴጥሮስንም ፦ ስምዖን ፡ ሆይ ፤ ተኝተሃልን ? አንዲት ፡ ሰዓት ፡ ስንኳ ፡ ልት ትጋ ፡ አልቻልህምን ? ፴፰ ወደ ፡ ፈተና ፡ እንዳትገቡ ፡ ትጉ ፡ ጸልዩም ፤ መንፈስስ ፡ ተዘጋጅታለች ፤ ሥጋ ፡ ግን ፡ ደካማ ፡ ነው ፡ አላቸው ፡፡ ፴፱ ደግሞም ፡ ሄዶ ፡ ያንኑ ፡ ቃል ፡ጸለየ ፡፡ ፵ ደግሞም ፡ መጥቶ ፡ ዓይኖቻቸው ፡ በእንቅልፍ ፡ ከብደው ፡ ነበርና ፡ ተኝተው ፡ አገኛቸው ፤ የሚመልሱለትንም ፡ አላ ወቁም ፡፡ ፵፩ ሦስተኛም ፡ መጥቶ ፦ እንግዲህስ ፡ ተኙ ፡ ዕረፉም ፤ ይበቃል ፤ ሰዓቲቱ ፡ ደረሰች ፤ እነሆ ፤ የሰው ፡ ልጅ ፡ በኃጢአተኞች ፡ እጅ ፡ ፵፪ አልፎ ፡ ይሰጣል ፡፡ ተነሡ ፤ እንሂድ ፤ እነሆ ፤ አሳልፎ ፡ የሚሰጠኝ ፡ ቀርቦአል ፡ አላቸው ፡፡

፵፫ ወዲያውም ፡ ገና ፡ ሲናገር ፡ ከአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ አንዱ ፡ ይሁዳ ፡ መጣ ፤ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ሰይፍና ፡ ጐመድ ፡ ይዘው ፡ ከካህናት ፡ አለቆችና ፡ ከጻፎች ፡ ከሽማግሌዎችም ፡ ዘንድ ፡ ፵፬ መጡ ፡፡ አሳልፎ ፡ የሚሰጠውም ፦ የምስመው ፡ እርሱ ፡ ነው ፤ ያዙት ፡ ተጠንቅቃችሁም ፡ ውሰ ዱት ፡ ብሎ ፡ ምልክት ፡ ሰጥቶአቸው ፡ ነበር ፡፡ ፵፭ መጥቶም ፡ ወዲያው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ቀረበና ፦ መምህር ፡ ሆይ ፤ መምህር ፡ ሆይ ፤ ብሎ ፡ሳመው ፤ ፵፮ እነርሱም ፡ እጃቸውን ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ጭነው ፡ ፵፯ ያዙት ፡፡ በአጠገብ ፡ ከቆሙት ፡ ግን ፡ አንዱ ፡ ሰይፉን ፡ መዘ ፡ የሊቀ ፡ ካህናቱን ፡ ባሪያ ፡ መታ ፡ ፵፰ ጆሮውንም ፡ ቈረጠ ፡፡ ኢየሱስም ፡ መልሶ ፦ ወንበዴ ፡ እንደምትይዙ ፡ ሰይፍና ፡ ጐመድ ፡ ፵፱ ይዛችሁ ፡ ልትይዙኝ ፡ መጣችሁን ? በመቅደስ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ እያስተማርሁ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ስኖር ፡ አልያዛችሁኝም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ መጻሕ ፍት ፡ ይፈጸሙ ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ሆነ ፡ አላቸው ፡፡ ፶ ሁሉም ፡ ትተውት ፡ ሸሹ ፡፡

፶፩ ዕርቃኑን ፡ በነጠላ ፡ የሸፈነ ፡ አንድ ፡ ጕበዝ ፡ ፶፪ ይከተለው ፡ ነበር ፤ ጕበዛዝቱም ፡ ያዙት ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ ነጠላውን ፡ ትቶ ፡ ዕራቁቱን ፡ ሸሸ ፡፡

፶፫ ኢየሱስንም ፡ ወደ ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ ወሰዱት ፤ የካህናት ፡ አለቆችም ፡ ሁሉ ፡ ሽማግሌዎችም ፡ ጻፎ ችም ፡ ተሰበሰቡ ፡፡ ፶፬ ጴጥሮስም ፡ እስከ ፡ ሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ ግቢ ፡ ውስጥ ፡ በሩቁ ፡ ተከተለው ፤ ከሎሌዎችም ፡ ጋር ፡ ተቀምጦ ፡ እሳት ፡ ይሞቅ ፡ ነበር ፡፡ ፶፭ የካህናት ፡ አለቆችም ፡ሸንጎውም ፡ ሁሉ ፡ እንዲገድሉት ፡ በኢየሱስ ፡ ላይ ፡ ምስክር ፡ ይፈ ልጉ ፡ ነበር ፤ አላገኙምም ፤ ፶፮ ብዙዎች ፡ በሐሰት ፡ ይመሰክሩበት ፡ ነበርና ፤ ምስክርነታቸው ፡ ግን ፡ አልተስማማም ፡፡ ፶፯-፶፰ ሰዎችም ፡ ተነሥተው ፦ እኔ ፡ ይህን ፡ በእጅ ፡ የተሠራውን ፡ቤተ ፡ መቅደስ ፡ አፈርሰዋለሁ ፡ በሦስት ፡ ቀንም ፡ሌላውን ፡ በእጅ ፡ ያልተሠራውን ፡ እሠራለሁ ፡ ሲል ፡ ሰማነው ፡ ብለው ፡ በሐሰት ፡ መሰከሩበት ፡፡ ፶፱ ምስክርነታ ቸውም ፡ እንዲሁ ፡ እንኳ ፡ አልተስማማም ፡፡ ፷ ሊቀ ፡ ካህናቱም ፡ በመካከላቸው ፡ ተነሥቶ ፦ አንዳች ፡ አትመልስምን ? እነዚህስ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ የሚመሰክሩብህ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብሎ ፡ ኢየሱስን ፡ ጠየቀው ፡፡ ፷፩ እርሱ ፡ ግን ፡ዝም ፡ አለ ፡ አንዳችም ፡ አልመለሰም ፡፡ ደግሞ ፡ ሊቀ ፡ ካህ ናቱ ፡ ጠየቀውና ፦ የቡሩክ ፡ ልጅ ፡ክርስቶስ ፡ አንተ ፡ ነህን ? አለው ፡፡ ፷፪ ኢየሱስም ፦ እኔ ፡ ነኝ ፤ የሰው ፡ ልጅም ፡ በኀይል ፡ ቀኝ ፡ ሊቀመጥ ፡ በሰማይም ፡ ደመና ፡ ሲመጣ ፡ ታያላችሁ ፡ አለ ፡፡ ፷፫ ሊቀ ፡ ካህናቱም ፡ ልብሱን ፡ ቀደደና ፦ ከእንግ ዲህ ፡ወዲህ ፡ ምስክሮችን ፡ ምን ፡ ያስፈልገናል ? ፷፬ ስድቡን ፡ ሰማችሁ ፤ ምን ፡ ይመስላችኋል ? አለ ፡፡ እነርሱም ፡ ሁሉ ፦ ሞት ፡ ይገባዋል ፡ ብለው ፡ ፈረዱበት ፡፡ ፷፭ አንዳንዶችም ፡ ይተፉበት ፡ ፊቱ ንም ፡ ሸፍነው ፡ ይጐስሙትና ፦ ትንቢት ፡ ተና ገር ፡ ይሉት ፡ ጀመር ፤ ሎሌዎችም ፡ በጥፊ ፡ እየ መቱ ፡ ወሰዱት ፡፡

፷፮ ጴጥሮስም ፡ በግቢ ፡ ውስጥ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ ሳለ ፡ ከሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ ገረዶች ፡ አንዲቱ ፡ መጣች ፤ ፷፯ ጴጥሮስም ፡ እሳት ፡ ሲሞቅ ፡ አይታ ፡ ተመለከተ ችውና ፦ አንተ ፡ ደግሞ ፡ ከናዝሬቱ ፡ ከኢየ ሱስ ፡ ጋር ፡ ነበርህ ፡ አለችው ፡፡ ፷፰ እርሱ ፡ ግን ፦ የምትዪውን ፡ አላውቅም ፡ አላስተውልምም ፡ ብሎ ፡ ካደ ፡፡ ወደ ፡ውጭም ፡ ወደ ፡ ደጅ ፡ ወጣ ፤ ዶሮም ፡ ጮኸ ፡፡ ፷፱ ገረዲቱም ፡ አይታው ፡ በዚያ ፡ ለቆሙት ፦ ይህም ፡ ከእነርሱ ፡ወገን ፡ ነው ፡ ስትል ፡ ሁለተኛ ፡ ትነግራቸው ፡ ጀመር ፡፡ ፸ እር ሱም ፡ ደግሞ ፡ ካደ ፡፡ ጥቂት ፡ ቈይተውም ፡ በዚያ ፡ የቆሙት ፡ ዳግመኛ ፡ ጴጥሮስን ፦ የገሊላ ፡ ሰው ፡ ነህና ፡ ከእነርሱ ፡ ወገን ፡ በእውነት ፡ ነህ ፡ አሉት ፡፡ ፸፩ እርሱ ፡ ግን ፦ ይህን ፡ የምትሉትን ፡ ሰው ፡ አላ ውቀውም ፡ ብሎ ፡ ይረገምና ፡ ይምል ፡ ጀመር ፡፡ ፸፪ ወዲያውም ፡ ዶሮ ፡ ሁለተኛ ፡ ጮኸ ፡፡ ጴጥሮስ ንም ፡ ኢየሱስ ፦ ዶሮ ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ሳይጮኽ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ትክደኛለህ ፡ ያለው ፡ ቃል ፡ ትዝ ፡ አለው ፡ ነገሩንም ፡ አስቦ ፡ አለቀሰ ፡፡

፲፬ ፡ ፴፪—፵፪ ፡ ማቴ ፡ ፳፮ ፡ ፴፮—፵፮ ፡ ሉቃ ፡ ፳፪ ፡ ፴፱—፵፮ ፡፡ ፴፫ ፡ ሉቃ ፡ ፳ ፡ ፴፯ ፡፡ ፴፬ ፡ ዮሐ ፡ ፲፪ ፡ ፳፯ ፡፡ ፴፮ ፡ ም ፡ ፲ ፡ ፴፰ ፡፡ ፵፫—፶ ፡ ማቴ ፡ ፳፮ ፡ ፵፯—፶፮ ፡ ሉቃ ፡ ፳፪ ፡ ፵፯—፶፫ ፡ ዮሐ ፡ ፲፰ ፡ ፫—፲፩ ፡፡ ፶፫—፷፭ ፡ ማቴ ፡ ፳፮ ፡ ፶፯—፷፰ ፡ ሉቃ ፡ ፳፪ ፡ ፶፬ ፡ ፷፫ ፡ ፷፭ ፡ ፷፬ ፡ ዮሐ ፡ ፲፰ ፡ ፲፪—፲፬ ፡ ፲፱—፳፬ ፡፡ ፶፰ ፡ ዮሐ ፡ ፪ ፡ ፲፱ ፡፡ ፷፪ ፡ ዘሌዋ ፡ ፳፬ ፡ ፲፮ ፡፡ ፷፮—፸፪ ፡ ማቴ ፡ ፳፮ ፡ ፷፱—፸፭ ፡ ሉቃ ፡ ፳፪ ፡ ፶፭—፷፪ ፡ ዮሐ ፡ ፲፰ ፡ ፲፭—፲፰ ፡ ፳፭—፳፯ ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ ወዲያውም ፡ ማለዳ ፡ የካህናት ፡ አለቆች ፡ ከሽማግሌዎችና ፡ ከጻፎች ፡ ከሸንጎውም ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ከተማከሩ ፡ በኋላ ፥ ኢየሱስን ፡ አሳስረው ፡ ወሰዱትና ፡ ለጲላጦስ ፡ አሳልፈው ፡ ሰጡት ። ፪ ጲላጦስም ፦ አንተ ፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ ነህን ? ብሎ ፡ ጠየቀው ። እርሱም ፦ አንተ ፡ አልህ ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ። ፫ የካህናት ፡ አለቆችም ፡ ብዙ ፡ ያሳጡት ፡ ነበር ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ አልመለሰም ። ፬ ጲላጦስም ፡ ደግሞ ፦ አንዳች ፡ አትመልስምን ? እነሆ ፥ በስንት ፡ ነገር ፡ ያሳጡሃል ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ። ፭ ኢየሱስም ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ጲላጦስ ፡ እስኪደነቅ ፡ ድረስ ፡ ምንም ፡ አልመለሰም ።

፮ በዚያም ፡ በዓል ፡ የለመኑትን ፡ አንድ ፡ እስረኛ ፡ ይፈታላቸው ፡ ነበር ። ፯ በዓመፅም ፡ ነፍስ ፡ ከገደሉት ፡ ከዓመፀኞች ፡ ጋር ፡ የታሰረ ፡ በርባን ፡ የተባለ ፡ ነበረ ። ፰ ሕዝቡም ፡ ወጥተው ፡ እንደ ፡ ልማዱ ፡ ያደርግላቸው ፡ ዘንድ ፡ እየጮኹ ፡ ይለምኑት ፡ ጀመር ። ፱ ጲላጦስም ፦ የአይሁድን ፡ ንጉሥ ፡ እፈታላችሁ ፡ ዘንድ ፡ ትወዳላችሁን ? ብሎ ፡ መለሰላቸው ፤ ፲ የካህናት ፡ አለቆች ፡ በቅንዓት ፡ አሳልፈው ፡ እንደ ፡ ሰጡት ፡ ያውቅ ፡ ነበርና ። ፲፩ የካህናት ፡ አለቆች ፡ ግን ፡ በርባንን ፡ በእርሱ ፡ ፈንታ ፡ ይፈታላቸው ፡ ዘንድ ፡ ሕዝቡን ፡ አወኩአቸው ። ፲፪ ጲላጦስም ፡ ዳግመኛ ፡ መልሶ ፦ እንግዲህ ፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ የምትሉትን ፡ ምን ፡ ላደርገው ፡ ትወዳላችሁ ? አላቸው ። ፲፫ እነርሱም ፡ ዳግመኛ ፦ ስቀለው ፡ እያሉ ፡ ጮኹ ። ፲፬ ጲላጦስም ፦ ምን ፡ ነው ? ያደረገው ፡ ክፋት ፡ ምንድር ፡ ነው ? አላቸው ። እነርሱ ፡ ግን ፦ ስቀለው ፡ እያሉ ፡ ጩኸት ፡ አበዙ ። ፲፭ ጲላጦስም ፡ የሕዝቡን ፡ ፈቃድ ፡ ሊያደርግ ፡ ወዶ ፡ በርባንን ፡ ፈታላቸው ፥ ኢየሱስንም ፡ ገርፎ ፡ እንዲሰቀል ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠ ።

፲፮ ወታደሮችም ፡ ፕራይቶሪዮን ፡ ወደሚባል ፡ ግቢ ፡ ውስጥ ፡ ወሰዱት ፥ ጭፍራውንም ፡ ሁሉ ፡ በአንድነት ፡ ጠሩ ። ፲፯ ቀይ ፡ ልብስም ፡ አለበሱት ፥ የእሾህ ፡ አክሊልም ፡ጐንጕነው ፡ ደፉበት ፤ ፲፰ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ ሰላም ፡ ለአንተ ፡ ይሁን ፡ እያሉም ፡ እጅ ፡ ይነሡት ፡ ጀመር ፤ ፲፱ ራሱንም ፡ በመቃ ፡ መቱት ፡ ተፉበትም ፥ ተንበርክከውም ፡ ሰገዱለት ። ፳ ከተዘባበቱበትም ፡ በኋላ ፡ ቀዩን ፡ ልብስ ፡ ገፈፉት ፥ ልብሱንም ፡ አለበሱት ፥ ሊሰቅሉትም ፡ ወሰዱት ።

፳፩ አንድ ፡ መንገድ ፡ አላፊም ፡ የእስክንድሮስና ፡ የሩፎስ ፡ አባት ፡ ስምዖን ፡ የተባለ ፡ የቀሬና ፡ ሰው ፡ ከገጠር ፡ ሲመጣ ፡ መስቀሉን ፡ ይሸከም ፡ ዘንድ ፡ ፳፪ አስገደዱት ። ትርጓሜውም ፡ የራስ ፡ ቅል ፡ ስፍራ ፡ ወደሚሆን ፡ ጎልጎታ ፡ ወደ ፡ ተባለ ፡ ስፍራ ፡ ወሰዱት ። ፳፫ ከርቤም ፡ የተቀላቀለበትን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ እንዲጠጣ ፡ ሰጡት ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ አልተቀበለም ። ፳፬ ሰቀሉትም ፥ ልብሱንም ፡ ማን ፡ ማን ፡ እንዲወስድ ፡ ዕጣ ፡ ተጣጥለው ፡ ተካፈሉ ። ፳፭ በሰቀሉትም ፡ ጊዜ ፡ ሦስት ፡ ሰዓት ፡ ነበረ ። ፳፮ የክሱ ፡ ጽሕፈትም ፦ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ የሚል ፡ ተጽፎ ፡ ነበር ። ፳፯ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ሁለት ፡ ወንበዴዎች ፡ አንዱን ፡ በቀኙ ፡ አንዱንም ፡ በግራው ፡ ሰቀሉ ። ፳፰ መጽሐፍም ፦ ከዓመፀኞች ፡ ጋር ፡ ተቈጠረ ፡ ያለው ፡ ተፈጸመ ። ፳፱ የሚያልፉትም ፡ ራሳቸውን ፡ እየነቀነቁ ፡ ይሰድቡት ፡ ነበርና ፦ ዋ ፥ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ የምታፈርስ ፡ በሦስት ፡ ቀንም ፡ የምትሠራ ፥ ፴ ከመስቀል ፡ ወርደህ ፡ ራስህን ፡ አድን ፡ አሉ ። ፴፩ እንዲሁም ፡ የካህናት ፡ አለቆች ፡ ደግሞ ፡ ከጻፎች ፡ ጋር ፡ አርስ ፡ በርሳቸው ፡ እየተዘባበቱ ፦ ሌሎችን ፡ አዳነ ፤ ራሱን ፡ ሊያድን ፡ አይችልም ፤ ፴፪ አይተን ፡ እናምን ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ክርስቶስ ፡ አሁን ፡ ከመስቀል ፡ ይውረድ ፡ አሉ ። ከእርሱም ፡ ጋር ፡ የተሰቀሉት ፡ ይነቅፉት ፡ ነበር ።

፴፫ ስድስት ፡ ሰዓትም ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፥ እስከ ፡ ዘጠኝ ፡ ሰዓት ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ጨለማ ፡ ሆነ ። ፴፬ በዘጠኝ ፡ ሰዓትም ፡ ኢየሱስ ፦ ኤሎሄ ፥ ኤሎሄ ፥ ላማ ፡ ሰበቅታኒ ? ብሎ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ጮኸ ፤ ትርጓሜውም ፡ አምላኬ ፥ አምላኬ ፥ ለምን ፡ተውኸኝ ? ማለት ፡ ነው ። ፴፭ በዚያም ፡ ከቆሙት ፡ ሰዎች ፡ ሰምተው ፦ እነሆ ፥ ኤልያስን ፡ ይጠራል ፡ አሉ ። ፴፮ አንዱም ፡ሮጦ ፡ ሆምጣጤ ፡ በሰፍነግ ፡ሞላ ፡ በመቃም ፡ አድርጎ ፦ ተዉ ፤ ኤልያስ ፡ ሊያወርደው ፡ ይመጣ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንዩ ፡ እያለ ፡ አጠጣው ። ፴፯ ኢየሱስም ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ጮኾ ፡ ነፍሱንም ፡ሰጠ ። ፴፰ የቤተ ፡ መቅደስም ፡ መጋረጃ ፡ ከላይ ፡ እስከ ፡ ታች ፡ ከሁለት ፡ ተቀደደ ። ፴፱ በዚያም ፡ በአንጻሩ ፡ የቆመ ፡ የመቶ ፡ አለቃ ፡ እንደዚህ ፡ ጮኾ ፡ ነፍሱን ፡ እንደ ፡ ሰጠ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፦ ይህ ፡ ሰው ፡ በእውነት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፡ አለ ።

፵፵፩ ሴቶችም ፡ ደግሞ ፡ በሩቅ ፡ ሆነው ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ፤ ከእነርሱም ፡ በገሊላ ፡ሳለ ፡ ይከተሉትና ፡ ያገለግሉት ፡ የነበሩ ፡ መግደላዊት ፡ ማርያም ፡ የታናሹ ፡ ያዕቆብና ፡ የዮሳም ፡ እናት ፡ ማርያም ፡ ሰሎሜም ፡ ነበሩ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ የወጡ ፡ ሌሎች ፡ ብዙዎች ፡ ሴቶች ፡ ነበሩ ።

፵፪ አሁንም ፡ በመሸ ፡ ጊዜ ፡ የሰንበት ፡ ዋዜማ ፡ የሆነ ፡ የማዘጋጀት ፡ ቀን ፡ ስለ ፡ ነበረ ፥ ፵፫ የከበረ ፡ አማካሪ ፡ የሆነ ፡ የአርማትያስ ፡ ዮሴፍ ፡ መጣ ፥

፲፭ ። ፩ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፩ ፡ ፪ ፤ ሉቃ. ፳፫ ፥ ፩ ፤ ዮሐ. ፲፰ ፥ ፳፰ ። ፪—፲፭ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፲፩—፳፮ ፤ ሉቃ. ፳፫ ፥ ፪ ፡ ፫ ፡ ፲፰—፳፭ ፤ ዮሐ. ፲፰ ፥ ፳፱—፵ ፤ ፲፱ ፥ ፲፮ ። ፩ ፤ ም. ፲፱ ፥ ፳፩ ፤ ኢሳ. ፶፫ ፥ ፯ ። ፲፮—፳ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፳፯—፴፩ ፤ ዮሐ. ፲፱ ፥ ፪ ፡ ፫ ። ፳፩ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፴፪ ፤ ሉቃ. ፳፫ ፥ ፳፮ ። ፳፪—፴፪ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፴፫—፵፬ ፤ ሉቃ. ፳፫ ፥ ፴፫—፵፫ ፡ ፵፱—፵፰ ፤ ዮሐ. ፲፱ ፥ ፲፯—፲፱ ፡ ፳፫ ፡ ፳፬ ፡ ፳፰—፴ ። ፳፬ ፤ መዝ. ፳፪ ፥ ፲፰ ። ፳፰ ፤ ኢሳ. ፶፫ ፥ ፲፪ ፤ ሉቃ. ፳፪ ፥ ፴፯ ። ፳፱ ፤ ም. ፲፬ ፥ ፶፰ ። ፴፬ ፤ መዝ. ፳፪ ፥ ፩ ። ፴፮ ፤ መዝ. ፷፱ ፥ ፳፩ ። ፴፫—፵፩ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፵፭—፶፮ ፤ ሉቃ. ፳፫ ፥ ፵፬—፵፱ ። ፵፩ ፤ ም. ፲፭ ፥ ፵፯ ። ፵፪—፵፯ ፤ ሉቃ. ፳፫ ፥ ፶፪—፶፮ ።

እርሱም ፡ ደግሞ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ ይጠባበቅ ፡ ነበር ፤ ደፍሮም ፡ ወደ ፡ ጲላጦስ ፡ ገብና ፡ የኢየሱስን ፡ ሥጋ ፡ ለመነው ። ፵፬ ጲላጦስም ፡ አሁኑን ፡ እንዴት ፡ ሞተ ፡ ብሎ ፡ ተደነቀ ፥ የመቶ ፡ አለቃውንም ፡ ጠርቶ ፡ ከሞተ ፡ ቆይቶአልን ? ብሎ ፡ ጠየቀው ፤ ፵፭ ከመቶ ፡ አለቃውም ፡ ፵፮ ተረድቶ ፡ በድኑን ፡ ለዮሴፍ ፡ ሰጠው ። በፍታም ፡ ገዝቶ ፡ አውርዶም ፡ በበፍታ ፡ ከፈነው ፡ ከዓለትም ፡ በተወቀረ ፡ መቃብር ፡ አኖረው ፥ በመቃ ፵፯ ብሩ ፡ ደጃፍም ፡ ድንጋይ ፡ አንከባለለ ። መግደላዊትም ፡ ማርያም ፡ የዮሳም ፡ እናት ፡ ማርያም ፡ ወዴት ፡ እንዳኖሩት ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ።

ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ ሰንበትም ፡ ካለፈ ፡ በኋላ ፡ መግደላዊት ፡ ማርያም ፡ የያዕቆብም ፡ እናት ፡ ማርያም ፡ ሰሎሜም ፡ ፪ መጥተው ፡ ሊቀቡት ፡ ሽቱ ፡ ገዙ ። ከሳምንቱም ፡ በፊተኛው ፡ ቀን ፡ እጅግ ፡ በማለዳ ፡ ፀሐይ ፡ ፫ ከወጣ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ መጡ ። እርስ ፡ በርሳቸውም ፡— ድንጋዩን ፡ ከመቃብር ፡ ደጃፍ ፡ ፬ ማን ፡ ያንከባልልልናል ? ይባባሉ ፡ ነበር ፤ ድንጋዩ ፡ እጅግ ፡ ትልቅ ፡ ነበርና ፤ አሻቅበውም ፡ አይተው ፡ ድንጋዩ ፡ ተንከባሎ ፡ እንደ ፡ ነበር ፡ ፭ ተመለከቱ ። ወደ ፡ መቃብሩም ፡ ገብተው ፡ ነጭ ፡ ልብስ ፡ የተጐናጸፈ ፡ ጐልማሳ ፡ በቀኝ ፡ በኩል ፡ ፮ ተቀምጦ ፡ አዩና ፡ ደነገጡ ። እርሱ ፡ ግን ፡— አትደንግጡ ፤ የተሰቀለውን ፡ የናዝሬቱን ፡ ኢየሱስን ፡ ትፈልጋላችሁ ፤ ተነሥቶአል ፥ በዚህ ፡ የለም ፤ እነሆ ፡ እርሱን ፡ ያኖሩበት ፡ ስፍራ ። ፯ ነገር ፡ ግን ፡ ሄዳችሁ ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ለጴጥሮስም ፡— ወደ ፡ ገሊላ ፡ ይቀድማችኋል ፤ እንደ ፡ ነገራችሁ ፡ በዚያ ፡ ታዩታላችሁ ፡ ብላችሁ ፡ ንገ ፰ ሩአቸው ፡ አላቸው ። መንቀጥቀጥና ፡ መደንገጥ ፡ ይዞአቸው ፡ ነበርና ፡ ወጥተው ፡ ከመቃብር ፡ ሸሹ ፤ ይፈሩ ፡ ነበርና ፡ ለማንም ፡ አንዳች ፡ አልነገሩም ።

እነርሱም ፡ ያዘዛቸውን ፡ ሁሉ ፡ ለጴጥሮስና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ላሉት ፡ በአጭሩ ፡ ተናገሩ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ኢየሱስ ፡ ራሱ ፡ ለዘላለም ፡ ድኅነት ፡ የሆነውን ፡ የማይለወጠውን ፡ ቅዱስ ፡ ወንጌል ፡ ከፀሐይ ፡ መውጫ ፡ እስከ ፡ መጥለቂያው ፡ ድረስ ፡ በእጃቸው ፡ ላከው ።

፱ ከሳምንቱም ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ማልዶ ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፥ አስቀድሞ ፡ ሰባት ፡ አጋንንት ፡ ላወጣላት ፡ ለመግደላዊት ፡ ማርያም ፡ ታየ ። ፲ እርስዋ ፡ ሄዳ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሆነው ፡ ለነበሩት ፡ ሲያዝኑና ፡ ሲያለቅሱ ፡ ሳሉ ፡ አወራችላቸው ፤ ፲፩ እነርሱም ፡ ሕያው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በእርስዋም ፡ እንደ ፡ ታያት ፡ ሲሰሙ ፡ አላመኑም ።

፲፪ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከእነርሱ ፡ ለሁለቱ ፡ ወደ ፡ ባላገር ፡ ሲሄዱ ፡ በመንገድ ፡ በሌላ ፡ መልክ ፡ ተገ ፲፫ ለጠ ፤ እነርሱም ፡ ሄደው ፡ ለሌሎቹ ፡ አወሩ ፤ እነዚያንም ፡ ደግሞ ፡ አላመኑአቸውም ።

፲፬ ኋላም ፡ በማዕድ ፡ ተቀምጠው ፡ ሳሉ ፡ ለአሥራ ፡ አንዱ ፡ ተገለጠ ፥ ተነሥቶም ፡ ያዩትን ፡ ስላላመኑአቸው ፡ አለማመናቸውንና ፡ የልባቸውን ፡ ጥንካሬ ፡ ነቀፈ ። ፲፭ እንዲህም ፡ አላቸው ፡— ወደ ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ ሂዱ ፡ ወንጌልንም ፡ ለፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ስበኩ ። ፲፮ ያመነ ፡ የተጠመቀም ፡ ይድናል ፥ ያላመነ ፡ ግን ፡ ይፈረድበታል ። ፲፯ ያመኑትንም ፡ እነዚህ ፡ ምልክቶች ፡ ይከተሉአቸዋል ፤ በስሜ ፡ አጋንንትን ፡ ያወጣሉ ፤ በአዲስ ፡ ቋንቋ ፡ ይናገራሉ ፤ ፲፰ እባቦችን ፡ ይይዛሉ ፥ የሚገድልም ፡ ነገር ፡ቢጠጡ ፡ አይጐዳቸውም ፤ እጃቸውን ፡ በድውዮች ፡ ላይ ፡ ይጭናሉ ፡ እነርሱም ፡ ይድናሉ ።

፲፱ ጌታ ፡ ኢየሱስም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ዐረገ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ቀኝ ፡ ተቀመጠ ። ፳ እነርሱም ፡ ወጥተው ፡ በየስፍራው ፡ ሁሉ ፡ ሰበኩ ፥ ጌታም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ይሠራ ፡ ነበር ፥ በሚከተሉትም ፡ ምልክቶች ፡ ቃሉን ፡ ያጸና ፡ ነበር ።

፲፮። ፩—፰ ፤ ማቴ. ፳፰ ፡ ፩—፰ ፤ ሉቃ. ፳፬ ፡ ፩—፲ ፤ ዮሐ. ፳ ፡ ፩ ። ፯ ፤ ማር. ፲፬ ፡ ፳፰ ። ፱ ፤ ዮሐ. ፳ ፡ ፲፬ ፤ ሉቃ. ፰ ፡ ፪ ። ፲፪ ፤ ሉቃ. ፳፬ ፡ ፲፫—፴፭ ። ፲፬ ፤ ሉቃ. ፳፬ ፡ ፴፮ ። ፲፭ ፤ ማቴ. ፳፰ ፡ ፲፱ ። ፲፮ ፤ ዮሐ. ፫ ፡ ፲፰ ፡ ፴፮ ። ፲፯ ፤ የሐዋ. ፲፮ ፡ ፲፰ ፤ ፪ ፡ ፬ ። ፲፰ ፤ ሉቃ. ፲ ፡ ፲፱ ፤ የሐዋ. ፳፰ ፡ ፫ ፡ ፭ ፡ ፰ ። ፲፱ ፤ የሐዋ. ፩ ፡ ፫—፱ ። ፳ ፤ የሐዋ. ፲፬ ፡ ፫ ።

# የጌታችን፡የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ወንጌል፡

# ቅዱስ፡ሉቃስ፡እንደ፡ጻፈው።

## ምዕራፍ ፩ ።

፩፡፪፡፫፡፬፡ የከበርህ፡ቴዎፍሎስ፡ሆይ፥ ከመጀመሪያው፡
በዓይን፡ያዩትና፡የቃሉ፡አገልጋዮች፡የሆኑት፡
እንዳስተላለፉልን፥ በኛ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ተፈጸ
መው ፡ ነገር ፡ ብዙዎች ፡ ታሪክን ፡ በየተራው ፡
ለማዘጋጀት ፡ ስለ ፡ ሞከሩ፥ እኔ ፡ ደግሞ ፡ ስለ ፡
ተማርኸው ፡ ቃል ፡ እርግጡን ፡ እንድታውቅ ፡
በጥንቃቄ ፡ ሁሉን ፡ ከመጀመሪያው ፡ ተከትዬ ፡
በየተራው፡ልጽፍልህ፡መልካም፡ሆኖ፡ታየኝ።
፭፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በሄሮድስ ፡ ዘመን ፡ ከአ
ብያ ፡ ክፍል ፡ የሆነ ፡ ዘካርያስ ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡
ካህን ፡ ነበረ ፤ ሚስቱም ፡ ከአሮን ፡ ልጆች ፡ ነበ
፮፡ ረች ፤ ስምዋም ፡ ኤልሳቤጥ ፡ ነበረ ። ሁለቱም ፡
በጌታ ፡ ትእዛዝና ፡ ሕግጋት ፡ ሁሉ ፡ ያለ ፡ ነቀፋ ፡
እየሄዱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ጻድቃን ፡ ነበሩ።
፯፡ ኤልሳቤጥም ፡ መካን ፡ ነበረችና ፡ ልጅ ፡ አል
ነበራቸውም ፤ ሁለቱም ፡ በዕድሜያቸው ፡ አርጅ
ተው ፡ ነበር ።
፰፡ እርሱም ፡ በክፍሉ ፡ ተራ ፡ በእግዚአብሔር ፡
፱፡ ፊት ፡ ሲያገለግል ፥ እንደ ፡ ክህነት ፡ ሥርዓት ፡
ወደ ፡ ጌታ ፡ ቤት ፡ መቅደስ ፡ ገብቶ ፡ ለማጠን ፡
፲፡ ዕጣ ፡ ደረሰበት ። በዕጣንም ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡ ፡
፲፩፡ ሁሉ ፡ በውጭ ፡ ቆመው ፡ ይጸልዩ ፡ ነበር ። የጌ
ታም ፡ መልአክ ፡ በዕጣኑ ፡ መሠዊያ ፡ ቀኝ ፡ ቆሞ ፡
፲፪፡ ታየው ። ዘካርያስም ፡ በየው ፡ ጊዜ ፡ ደነገጠ ፥
፲፫፡ ፍርሃትም ፡ ወደቀበት ። መልአኩም ፡ እንዲህ ፡
አለው ፦ ዘካርያስ ፡ ሆይ ፥ ጸሎትህ ፡ ተሰምቶልሃ
ልና ፡ አትፍራ ፤ ሚስትህ ፡ ኤልሳቤጥም ፡ ወንድ ፡
ልጅ ፡ ትወልድልሃለች ፥ ስሙንም ፡ ዮሐንስ ፡ ትለ
፲፬፡ ዋለህ ። ደስታና ፡ ተድላም ፡ ይሆንልሃል ፥ በመ
፲፭፡ ወለዱም ፡ ብዙዎች ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ። በጌታ ፡
ፊት ፡ ታላቅ ፡ ይሆናልና ፥ የወይን ፡ ጠጅና ፡ የሚ
ያሰክር ፡ መጠጥ ፡ አይጠጣም ፤ ገናም ፡ በእናቱ ፡
ማኅፀን ፡ ሳለ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ይሞላበታል ፤
፲፮፡ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ብዙዎችን ፡ ወደ ፡ ጌታ ፡
፲፯፡ ወደ ፡ አምላካቸው ፡ ይመልሳል ። እርሱም ፡
የተዘጋጁትን ፡ ሕዝብ ፡ ለጌታ ፡ እንዲያሰናዳ ፥
የአባቶችን ፡ ልብ ፡ ወደ ፡ ልጆች ፡ የማይታዘዙ
ትንም ፡ ወደ ፡ ጻድቃን ፡ ጥበብ ፡ ይመልስ ፡ ዘንድ ፡
በኤልያስ ፡ መንፈስና ፡ ኃይል ፡ በፊቱ ፡ ይሄዳል ።
፲፰፡ ዘካርያስም ፡ መልአኩን ፦ እኔ ፡ ሽማግሌ ፡ ነኝ ፡
ሚስቴም ፡ በዕድሜዋ ፡ አርጅታለችና ፡ ይህን ፡
፲፱፡ በምን ፡ አውቃለሁ ? አለው ። መልአኩም ፡
መልሶ ፦ እኔ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የምቆ
መው ፡ ገብርኤል ፡ ነኝ ፥ እንድናገርህም ፡ ይህ
ችንም ፡ የምሥራች ፡ እንድሰብክልህ ፡ ተልኬ ፡
ነበር ፤ እነሆም ፥ በጊዜው ፡ የሚፈጸመውን ፡ ፳፡
ቃሌን ፡ ስላላመንህ ፥ ይህ ፡ ነገር ፡ እስከሚሆን ፡
ቀን ፡ ድረስ ፡ ድዳ ፡ ትሆናለህ ፡ መናገርም ፡ አት
ችልም ፡ አለው ። ሕዝቡም ፡ ዘካርያስን ፡ ይጠብ ፳፩፡
ቁት ፡ ነበር ፤ በቤተ ፡ መቅደስም ፡ ውስጥ ፡ ስለ ፡
ዘገየ ፡ ይደነቁ ፡ ነበር ። በወጣም ፡ ጊዜ ፡ ሊነግ ፳፪፡
ራቸው ፡ አልቻለም ፥ በቤተ ፡ መቅደስም ፡ ራእይ ፡
እንዳየ ፡ አስተዋሉ ፤ እርሱም ፡ ይጠቅሳቸው ፡
ነበር ፤ ድዳም ፡ ሆኖ ፡ኖረ ። የማገልገሉም ፡ ፳፫፡
ወራት ፡ ሲፈጸም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ።
ከዚህም ፡ ወራት ፡ በኋላ ፡ ሚስቱ ፡ ኤልሳቤጥ ፡ ፳፬፡፳፭፡
ፀነሰችና ፦ ነቀፌታዬን ፡ ከሰው ፡ መካከል ፡ ያስ
ወግድልኝ ፡ ዘንድ ፡ ጌታ ፡ በተመለከተበት ፡
ወራት ፡ እንዲህ ፡ አድርጎልኛል ፡ በትል ፡ ራስ
ዋን ፡ አምስት ፡ ወር ፡ ሰወረች ።
በስድስተኛውም ፡ ወር ፡ መልአኩ ፡ ገብር ፳፮፡
ኤል ፡ ናዝሬት ፡ ወደምትባል ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡
ከተማ ፥ ከዳዊት ፡ ወገን ፡ ለሆነው ፡ ዮሴፍ ፡ ፳፯፡
ለሚባል ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ታጨች ፡ ወደ ፡ አንዲት ፡
ድንግል ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ተላከ ፥ የድ
ንግሊቱም ፡ ስም ፡ ማርያም ፡ ነበረ ። መልአ ፳፰፡
ኩም ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ገብቶ ፦ ደስ ፡ ይበልሽ ፥
ጸጋ ፡ የሞላብሽ ፡ ሆይ ፥ ጌታ ፡ ከአንቺ ፡ ጋር ፡
ነው ፤ አንቺ ፡ ከሴቶች ፡ መካከል ፡ የተባረክሽ ፡
ነሽ ፡ አላት ። እርስዋም ፡ በየችው ፡ ጊዜ ፡ ከን ፳፱፡
ግግሩ ፡ በጣም ፡ ደነገጠችና ፦ ይህ ፡ እንዴት ፡
ያለ ፡ ሰላምታ ፡ ነው ? ብላ ፡ አሰበች ። መልአ ፴፡
ኩም ፡ እንዲህ ፡ አላት ፦ ማርያም ፡ ሆይ ፥ በእ
ግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ጸጋ ፡ አግኝተሻልና ፡ አት
ፍሪ ። እነሆም ፥ ትፀንሻለሽ ፡ ወንድ ፡ ልጅም ፡ ፴፩፡
ትወልጃለሽ ፥ ስሙንም ፡ ኢየሱስ ፡ ትዪዋለሽ ።
እርሱ ፡ ታላቅ ፡ ይሆናል ፡ የልዑል ፡ ልጅም ፡ ፴፪፡
ይባላል ፥ ጌታ ፡ አምላክም ፡ የአባቱን ፡ የዳዊትን ፡
ዙፋን ፡ ይሰጠዋል ፤ በያዕቆብ ፡ ቤትም ፡ ላይ ፡ ፴፫፡
ለዘላለም ፡ ይነግሣል ፥ ለመንግሥቱም ፡ መጨ
ረሻ ፡ የለውም ። ማርያምም ፡ መልአኩን ፦ ፴፬፡
ወንድ ፡ ስለማላውቅ ፡ ይህ ፡ እንዴት ፡ ይሆናል ?
አለችው ። መልአኩም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ ፴፭፡
አላት ፦ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በአንቺ ፡ ላይ ፡ ይመ
ጣል ፥ የልዑልም ፡ ኃይል ፡ ይጸልልሻል ፤ ስለ
ዚህ ፡ ደግሞ ፡ ከአንቺ ፡ የሚወለደው ፡ ቅዱሱ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ይባላል ። እነሆም ፡ ፴፮፡
ዘመድሽ ፡ ኤልሳቤጥ ፥ እርስዋ ፡ ደግሞ ፡ በእር

---

፩። ፭፡ ፩ ዜና ፳፬ ፥ ፲ ። ፮፡ ዘፍጥ ፯ ፥ ፩ ፥ ፲ ። ፲፩፡ ዘፀአ ፴ ፥ ፩ ፥ ፯ ። ፲፭፡ ዘኍል ፮ ፥ ፫ ፥ ማቴ ፲፩ ፥ ፲፩ ።
፲፯፡ ሚል ፬ ፥ ፭ ፥ ፮ ፥ ማቴ ፲፩ ፥ ፲፬ ። ፲፱፡ ዳን ፰ ፥ ፲፮ ፥ ፱ ፥ ፳፩ ። ፳፯፡ ማቴ ፩ ፥ ፲፰ ። ፴፩፡ ኢሳ ፯ ፥
፲፬ ፥ ማቴ ፩ ፥ ፳፩ ፥ ፳፭ ። ፴፪፡ ፴፫፡ ፪ ሳሙ ፯ ፥ ፲፩ ፥ ዳን ፪ ፥ ፵፬ ፥ ሚክ ፬ ፥ ፯ ። ፴፭፡ ማቴ ፩ ፥ ፳ ፥ ዮሐ ፩ ፥ ፴፬ ።

ጅናዋ ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ፀንሳለች ÷ ለእርስዋም ፡ መካን ፡ ትባል ፡ ለነበረችው ፡ ይህ ፡ ስድስተኛ ፡
፴፯ ወር ፡ ነው ፤ ለእግዚአብሔር ፡ የሚሳነው ፡ ነገር ፡
፴፰ የለምና ። ማርያምም ፡— እነሆኝ ፡ የጌታ ፡ ባሪያ ፤ እንደ ፡ ቃልህ ፡ ይሁንልኝ ፡ አለች ። መልአኩም ፡ ከእርስዋ ፡ ሄደ ።

፴፱ ማርያምም ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ ተነሥታ ፡ ወደ ፡ ተራራማው ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ከተማ ፡
፵ ፈጥና ፡ ወጣች ÷ ወደ ፡ ዘካርያስም ፡ ቤት ፡ ገብታ ፡
፵፩ ኤልሳቤጥን ፡ ተሳለመቻት ። ኤልሳቤጥም ፡ የማርያምን ፡ ሰላምታ ፡ በሰማች ፡ ጊዜ ፡ ፅንሱ ፡ በማኅፀንዋ ፡ ውስጥ ፡ ዘለለ ፤ በኤልሳቤጥም ፡ መን
፵፪ ፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሞላባት ÷ በታላቅ ፡ ድምፅም ፡ ጮኻ ፡ እንዲህ ፡ አለች ፡— አንቺ ፡ ከሴቶች ፡ መካከል ፡ የተባረክሽ ፡ ነሽ ÷ የማኅፀንሽም ፡ ፍሬ ፡
፵፫ የተባረከ ፡ ነው ። የጌታዬ ፡ እናት ፡ ወደ ፡ እኔ ፡
፵፬ ትመጣ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ይሆንልኛል ? እነሆ ÷ የሰላምታሽ ፡ ድምፅ ፡ በጆሮዬ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡
፵፭ ፅንሱ ፡ በማኅፀኔ ፡ በደስታ ፡ ዘሎአልና ። ከጌታ ፤ የተነገረላት ፡ ቃል ፡ ይፈጸማልና ፡ ያመነች ፡ ብፅ
፵፮ ዕት ፡ ናት ። ማርያምም ፡ እንዲህ ፡ አለች ፡—

፵፯ ነፍሴ ፡ ጌታን ፡ ታከብረዋለች ÷ መንፈሴም ፡ በአምላኬ ፡ በመድኃኒቴ ፡ ሐሴት ፡ ታደር
፵፰ ጋለች ፤ የባሪያይቱን ፡ ውርደት ፡ ተመልክ ቶአልና ። እነሆም ÷ ከዛሬ ፡ጀምሮ ፡ ትው
፵፱ ልድ ፡ ሁሉ ፡ ብፅዕት ፡ ይሉኛል ፤ ብርቱ ፡ የሆነ ፡ እርሱ ፡ በእኔ ፡ ታላቅ ፡ ሥራ ፡ አድርጎአ
፶ ልና ፤ ስሙም ፡ ቅዱስ ፡ ነው ። ምሕረቱም ፡ ለሚፈሩት ፡ እስከ ፡ ትውልድና ፡ ትውልድ ፡
፶፩ ይኖራል ። በክንዱ ፡ ኃይል ፡ አድርጎአል ፤ ትዕቢተኞችን ፡ በልባቸው ፡ አሳብ ፡ በትና
፶፪ አል ፤ ገዢዎችን ፡ ከዙፋናቸው ፡ አዋርዶ አል ፤ ትሑታንንም ፡ ከፍ ፡ አድርጎአል ፤
፶፫ የተራቡትን ፡ በበጎ ፡ ነገር ፡ አጥግቦአል ፤ ባለ ጠጎችንም ፡ ባዶአቸውን ፡ ሰዶአቸዋል ።
፶፬፡፶፭ ለአባቶቻችን ፡ እንደ ፡ ተናገረ ÷ ለአብርሃ ምና ፡ ለዘሩ ፡ ለዘላለም ፡ ምሕረቱ ፡ ትዝ ፡ እያ ለው ፡ እስራኤልን ፡ ብላቴናውን ፡ ረድቶ አል ።

፶፮ ማርያምም ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ የሚያህል ፡ በእርስዋ ፡ ዘንድ ፡ ተቀመጠች ፡ ወደ ፡ ቤትዋም ፡ ተመለ ሰች ።

፶፯ የኤልሳቤጥም ፡ የመውለጃዋ ፡ ጊዜ ፡ ደረሰ ÷
፶፰ ወንድ ፡ ልጅም ፡ ወለደች ። ጎረቤቶችዋም ፡ ዘመዶችዋም ፡ ጌታ ፡ ምሕረቱን ፡ እንዳገነነላት ፡ ሰምተው ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ ደስ ፡ አላቸው ።
፶፱ በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ ሕፃኑን ፡ ሊገርዙት ፡ መጡ ÷ በአባቱም ፡ ስም ፡ ዘካርያስ ፡ ሊሉት ፡
፷ ወደዱ ። እናቱ ፡ ግን ፡ መልሳ ፡— አይሆንም ÷
፷፩ ዮሐንስ ፡ ይባል ፡ እንጂ ፡ አለች ። እነርሱም ፡— ከወገንሽ ፡ ማንም ፡ በዚህ ፡ ስም ፡ የተጠራ ፡ የለም ፡
፷፪ አሉአት ። አባቱንም ፡ ማን ፡ ሊባል ፡ እንዲወድ ፡
፷፫ ጠቀሱት ። ብራናም ፡ ለምኖ ፡— ስሙ ፡ ዮሐ ንስ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ጻፈ ። ሁሉም ፡ አደነቁ ።
፷፬ ያንጊዜም ፡ አፉ ፡ ተከፈተ ፡ መላሱም ፡ ተፈታ ፡
፷፭ እግዚአብሔርንም ፡ እየባረከ ፡ ተናገረ ። ለጎረ ቤቶቻቸውም ፡ ሁሉ ፡ ፍርሃት ፡ ሆነ ፤ ይህም ፡ ሁሉ ፡ ነገር ፡ በይሁዳ ፡ በተራራማው ፡ አገር ፡
፷፮ ሁሉ ፡ ተወራ ፤ የሰሙትም ፡ ሁሉ ፡— እንኪያ ፡ ይህ ፡ ሕፃን ፡ ምን ፡ ይሆን ? እያሉ ፡ በልባቸው ፡ አኖሩት ፤ የጌታ ፡ እጅ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረችና ።
፷፯ አባቱ ፡ ዘካርያስም ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሞላበ ትና ፡ ትንቢት ፡ ተናገረ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፡—

፷፰ የእስራኤል ፡ ጌታ ፡ አምላክ ፡ ይባረክ ÷ ጐብኝቶ ፡ ለሕዝቡ ፡ ቤዛ ፡ አድርጎአልና ፤
፷፱፡፸ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ በነበሩት ፡ በቅዱሳን ፡ ነቢ ያት ፡ አፍ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ÷ በብላቴናው ፡ በዳዊት ፡ ቤት ፡ የመዳን ፡ ቀንድን ፡ አስነሥ
፸፩ ቶልናል ፤ ማዳኑም ፡ ከወደረኞቻችንና ፡
፸፪፡፸፫ ከሚጠሉን ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ ነው ፤ እንደዚህ ፡ ለአባቶቻችን ፡ ምሕረት ፡ አደረገ ፤ ለአባ ታችን ፡ ለአብርሃምም ፡ የማለውን ፡ መሐ
፸፬፡፸፭ ላውን ፡ ቅዱሱን ፡ኪዳን ፡ አሰበ ፤ በእር ሱም ፡ ከጠላቶቻችን ፡ እጅ ፡ ድነን ፡ በዘመ ናችን ፡ ሁሉ ፡ ያለ ፡ ፍርሃት ፡ በቅድስናና ፡ በጽድቅ ፡ በፊቱ ፡ እንድናገለግለው ፡ ሰጠን ።
፸፮ ደግሞም ፡ አንተ ፡ ሕፃን ፡ ሆይ ÷ የልዑል ፡ ነቢይ ፡ ትባላለህ ÷ መንገዱን ፡ ልትጠርግ ፡
፸፯ በጌታ ፡ ፊት ፡ ትሄዳለህና ፤ እንደዚህም ፡ የኃጢአታቸው ፡ ስርየት ፡ የሆነውን ፡ የመ ዳን ፡ እውቀት ፡ ለሕዝቡ ፡ ትሰጣለህ ፤
፸፰ ይህም ፡ ከላይ ፡ የመጣ ፡ ብርሃን ፡ በጐበኘ ብት ፡ በአምላካችን ፡ ምሕረትና ፡ ርኅራኄ ፡
፸፱ ምክንያት ፡ ነው ፤ ብርሃኑም ፡ በጨለማና ፡ በሞት ፡ ጥላ ፡ ተቀምጠው ፡ ላሉት ፡ ያበ ራል ፡ እግሮቻችንንም ፡ በሰላም ፡ መንገድ ፡ ያቀናል ።

፹ ሕፃኑም ፡ አደገ ፡ በመንፈስም ፡ ጠነከረ ÷ ለእስ ራኤልም ፡ እስከ ፡ ታየበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ በም ድረ ፡ በዳ ፡ ኖረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ በዚያም ፡ ወራት ፡ ዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ እንዲጻፍ ፡
፪ ከአውግስጦስ ፡ ቄሣር ፡ ትእዛዝ ፡ ወጣች ። ቄሬ ኔዎስ ፡ በሶርያ ፡ አገር ፡ ገዥ ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፡ ይህ ፡
፫ የመጀመሪያ ፡ጽሕፈት ፡ ሆነ ። ሁሉም ፡ እያን

፴፯ ፤ ዘፍጥ. ፲፰ ÷ ፲፬ ፤ ማቴ. ፲፱ ÷ ፳፮ ። [illegible]

ዳንዱ ፡ ይጻፍ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ከተማው ፡ ሄደ ።
፬ ዮሴፍም ፡ ደግሞ ፡ ከዳዊት ፡ ቤትና ፡ ወገን ፡ ስለ ፡
ነበረ ፡ ከገሊላ ፡ ከናዝሬት ፡ ከተማ ፡ ተነሥቶ ፡ ቤተ ፡
ልሔም ፡ ወደምትባል ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ከተማ ፡
ወደ ፡ ይሁዳ ፥ ፀንሳ ፡ ከነበረች ፡ ከእጮኛው ፡
፭ ከማርያም ፡ ጋር ፡ ይጻፍ ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ። በዚ
፮ ያም ፡ ሳሉ ፡ የመውለጃዋ ፡ ወራት ፡ ደረሰ ፥ የበ
ኵር ፡ ልጅዋንም ፡ ወለደች ፥ በመጠቅለያም ፡
ጠቀለለችው ፤ በእንግዶችም ፡ ማደሪያ ፡ ስፍራ ፡
ስላልነበራቸው ፡ በግርግም ፡ አስተኛችው ።
፰ በዚያም ፡ ምድር ፡ መንጋቸውን ፡ በሌሊት ፡
ሲጠብቁ ፡ በሜዳ ፡ ያደሩ ፡ እረኞች ፡ ነበሩ ።
፱ እነሆም ፥ የጌታ ፡ መልአክ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡
ቀረበ ፡ የጌታ ፡ ክብርም ፡ በዙሪያቸው ፡ አበራ ፥
፲ ታላቅ ፡ ፍርሃትም ፡ ፈሩ ። መልአኩም ፡ እንዲህ ፡
አላቸው ፦ እነሆ ፥ ለሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ የሚሆን ፡
ታላቅ ፡ ደስታ ፡ የምሥራች ፡ እነግራችኋለሁና ፡
፲፩ አትፍሩ ፤ ዛሬ ፡ በዳዊት ፡ ከተማ ፡ መድኃኒት ፡
እርሱም ፡ ክርስቶስ ፡ ጌታ ፡ የሆነ ፡ ተወልዶላችኋ
፲፪ ልና ። ይህም ፡ ምልክት ፡ ይሆንላችኋል ፤ ሕፃን ፡
ተጠቅልሎ ፡ በግርግምም ፡ ተኝቶ ፡ ታገኛላችሁ ።
፲፫ ድንገትም ፡ ብዙ ፡ የሰማይ ፡ ሠራዊት ፡ ከመል
አኩ ፡ ጋር ፡ ነበሩ ። እግዚአብሔርንም ፡ እያመ
፲፬ ሰገኑ ፦ ክብር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በአርያም ፡
ይሁን ፡ ሰላምም ፡ በምድር ፡ ለሰውም ፡ በጎ ፡
ፈቃድ ፡ አሉ ።
፲፭ መላእክትም ፡ ከእነርሱ ፡ ተለይተው ፡ ወደ ፡
ሰማይ ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፥ እረኞቹ ፡ እርስ ፡ በር
ሳቸው ፦ እንግዲህ ፡ እስከ ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፡
ድረስ ፡ እንሂድ ፡ እግዚአብሔርም ፡ የገለጠል
ንን ፡ ይህን ፡ የሆነውን ፡ ነገር ፡ እንይ ፡ ተባባሉ ።
፲፮ ፈጥነውም ፡ መጡ ፡ ማርያምንና ፡ ዮሴፍን ፡ ሕፃ
፲፯ ኑንም ፡ በግርግም ፡ ተኝቶ ፡ አገኙ ። አይተ
ውም ፡ ስለዚህ ፡ ሕፃን ፡ የተነገረላቸውን ፡ ነገር ፡
፲፰ ገለጡ ። የሰሙትም ፡ ሁሉ ፡ እረኞቹ ፡ በነገሩ
፲፱ አቸው ፡ ነገር ፡ አደነቁ ፤ ማርያም ፡ ግን ፡ ይህን ፡
ነገር ፡ ሁሉ ፡ በልብዋ ፡ እያሰበች ፡ ትጠብቀው ፡
፳ ነበር ። እረኞችም ፡ እንደ ፡ ተባለላቸው ፡ ስለ ፡
ሰሙትና ፡ ስላዩት ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እያ
መሰገኑና ፡ እያከበሩ ፡ ተመለሱ ።
፳፩ ሊገርዙት ፡ ስምንት ፡ ቀን ፡ በሞላ ፡ ጊዜ ፥ በማ
ኅፀን ፡ ሳይረገዝ ፡ በመልአኩ ፡ እንደ ፡ ተባለ ፥
ስሙ ፡ ኢየሱስ ፡ ተብሎ ፡ ተጠራ ።
፳፪ ፳፫ ፳፬ እንደ ፡ ሙሴም ፡ ሕግ ፡ የመንጻታቸው ፡ ወራት ፡
በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፥ በጌታ ፡ ሕግ ፦ የእናቱን ፡
ማኅፀን ፡ የሚከፍት ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ ለጌታ ፡ የተ
ቀደሰ ፡ ይባላል ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ በጌታ ፡
ፊት ፡ ሊያቆሙት ፥ በጌታም ፡ ሕግ ፦ ሁለት ፡
ዋሊያ ፡ ወይም ፡ ሁለት ፡ የርግብ ፡ ጫጩቶች ፡
እንደ ፡ ተባለ ፥ መሥዋዕት ፡ ሊያቀርቡ ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ወሰዱት ። ፳፭ እነሆም ፥ በኢየሩሳ
ሌም ፡ ስምዖን ፡ የሚባል ፡ ሰው ፡ ነበረ ፥ ይህም ፡
ሰው ፡ የእስራኤልን ፡ መጽናናት ፡ ይጠባበቅ ፡
ነበር ፤ ጻድቅና ፡ ትጉህም ፡ ነበረ ፥ መንፈስ ፡ ቅዱ
ስም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ነበረ ። ፳፮ በጌታም ፡ የተቀ
ባውን ፡ ሳያይ ፡ ሞትን ፡ እንዳያይ ፡ በመንፈስ ፡
ቅዱስ ፡ ተረድቶ ፡ ነበር ። ፳፯ በመንፈስም ፡ ወደ ፡
መቅደስ ፡ ወጣ ፤ ወላጆቹም ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡
ልማድ ፡ ያደርጉለት ፡ ዘንድ ፡ ሕፃኑን ፡ ኢየሱ
ስን ፡ በአስገቡት ፡ ጊዜ ፥ ፳፰ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ ተቀ
ብሎ ፡ አቀፈው ፡ እግዚአብሔርንም ፡ እየባረከ ፡
እንዲህ ፡ አለ ፦

፳፱ ጌታ ፡ ሆይ ፥ አሁን ፡ እንደ ፡ ቃልህ ፡ ባሪያ
ህን ፡ በሰላም ፡ ታሰናብተዋለህ ፤ ፴ ፴፩ ዓይኖቼ ፡
በሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ያዘጋጀኸውን ፡ ማዳ
ንህን ፡ አይተዋልና ፤ ፴፪ ይህም ፡ ለአሕዛብ ፡
ሁሉን ፡ የሚገልጥ ፡ ብርሃን ፡ ለሕዝብህም ፡
ለእስራኤል ፡ ክብር ፡ ነው ።

፴፫ ዮሴፍና ፡ እናቱም ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ በተባለው ፡
ነገር ፡ ይደነቁ ፡ ነበር ። ፴፬ ፴፭ ስምዖንም ፡ ባረካቸው ፡
እናቱን ፡ ማርያምንም ፦ እነሆ ፥ የብዙዎች ፡
ልብ ፡ አሳብ ፡ ይገለጥ ፡ ዘንድ ፥ ይህ ፡ በእስራኤል ፡
ላሉት ፡ ለብዙዎቹ ፡ ለመውደቃቸውና ፡ ለመነሣ
ታቸው ፡ ለሚቃወሙትም ፡ ምልክት ፡ ተሾሞ
አል ፥ በአንቺም ፡ ደግሞ ፡ በነፍስሽ ፡ ሰይፍ ፡ ያል
ፋል ፡ አላት ።

፴፮ ከአሴር ፡ ወገንም ፡ የምትሆን ፡ የፋኑኤል ፡
ልጅ ፡ ሐና ፡ የምትባል ፡ አንዲት ፡ ነቢይት ፡ ነበ
ረች ፤ እርስዋም ፡ ከድንግልናዋ ፡ ጀምራ ፡ ከባ
ልዋ ፡ ጋር ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ኖረች ፤ ፴፯ እርስዋም ፡
ሰማኒያ ፡ አራት ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ መበለት ፡ ሆና ፡
በጣም ፡ አርጅታ ፡ ነበር ፤ በጾምና ፡ በጸሎትም ፡
ሌሊትና ፡ ቀን ፡ እያገለገለች ፡ ከመቅደስ ፡ አትለ
ይም ፡ ነበር ። ፴፰ በዚያችም ፡ ሰዓት ፡ ቀርባ ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ አመሰገነች ፤ የኢየሩሳሌምንም ፡
ቤዛ ፡ ለሚጠባበቁ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ትናገር ፡
ነበር ።

፴፱ ሁሉንም ፡ እንደ ፡ ጌታ ፡ ሕግ ፡ ከፈጸሙ ፡ በኋላ ፥
ወደ ፡ ገሊላ ፡ ወደ ፡ ከተማቸው ፡ ወደ ፡ ናዝሬት ፡
ተመለሱ ። ፵ ሕፃኑም ፡ አደገ ፥ ጥበብም ፡ ሞልቶ
በት ፡ በመንፈስ ፡ ጠነከረ ፤ የእግዚአብሔርም ፡
ጸጋ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ነበረ ።

፵፩ ወላጆቹም ፡ በየዓመቱ ፡ በፋሲካ ፡ በዓል ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ይወጡ ፡ ነበር ። ፵፪ የአሥራ ፡ ሁለት ፡
ዓመት ፡ ልጅ ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፥ እንደ ፡ በዓሉ ፡ ሥር
ዓት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወጡ ፤ ፵፫ ቀኖቹንም ፡ ከፈ
ጸሙ ፡ በኋላ ፥ ሲመለሱ ፡ ብላቴናው ፡ ኢየሱስ ፡
በኢየሩሳሌም ፡ ቀርቶ ፡ ነበር ፥ ዮሴፍም ፡ እናቱም ፡
አላወቁም ፡ ነበር ። ፵፬ ከመንገደኞች ፡ ጋር ፡ የነ
በረ ፡ ስለ ፡ መሰላቸው ፡ የአንድ ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡

[illegible]

ሄዱ ፥ ከዘመዶቻቸውም ፡ ከሚያውቋቸውም ፡ ዘንድ ፡ ፈለጉት ፤ [፵፭] ባጡትም ፡ ጊዜ ፡ እየፈለጉት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ። [፵፮] ከሦስት ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ በመምህራን ፡ መካከል ፡ ተቀምጦ ፡ ሲሰማቸውም ፡ ሲጠይቃቸውም ፡ በመቅደስ ፡ አገኙት ፤ [፵፯] የሰሙትም ፡ ሁሉ ፡ በማስተዋሉና ፡ በመልሱ ፡ ተገረሙ ። [፵፰] ባዩትም ፡ ጊዜ ፡ ተገረሙ ፥ እናቱም ፦ ልጄ ፡ ሆይ ፥ ስለ ምን ፡ እንዲህ ፡ አደረግህብን ? እነሆ ፥ አባትህና ፡ እኔ ፡ እየተጨነቅን ፡ ስንፈልግህ ፡ ነበርን ፡ አለችው ። [፵፱] እርሱም ፦ ስለ ፡ ምን ፡ ፈለጋችሁኝ ? በአባቴ ፡ ቤት ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ እንዲገባኝ ፡ አላወቃችሁምን ? አላቸው ። [፶] እነርሱም ፡ የተናገራቸውን ፡ ነገር ፡ አላስተዋሉም ። [፶፩] ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ወርዶ ፡ ወደ ፡ ናዝሬት ፡ መጣ ፥ ይታዘዝላቸውም ፡ ነበር ። እናቱም ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በልብዋ ፡ ትጠብቀው ፡ ነበር ።

[፶፪] ኢየሱስም ፡ ደግሞ ፡ በጥበብና ፡ በቁመት ፡ በሞገስም ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ ያድግ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

[፩] ጢባርዮስ ፡ ቄሣርም ፡ በነገሠ ፡ በአሥራ ፡ አምስተኛይቱ ፡ ዓመት ፥ ጴንጤናዊው ፡ ጲላጦስም ፡ በይሁዳ ፡ ሲገዛ ፥ ሄሮድስም ፡ በገሊላ ፡ የአራተኛው ፡ ክፍል ፡ ገዥ ፥ ወንድሙ ፡ ፊልጶስም ፡ በኢጡርያስ ፡ በትራኮኒዶስም ፡ አገር ፡ የአራተኛው ፡ ክፍል ፡ ገዥ ፥ ሊሳኒዮስም ፡ በሳቢላኒስ ፡ የአራተኛው ፡ ክፍል ፡ ገዥ ፡ ሆነው ፡ ሳሉ ፥ [፪] ሐናና ፡ ቀያፋም ፡ ሊቃነ ፡ ካህናት ፡ ሳሉ ፥ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ዘካርያስ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ዮሐንስ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ መጣ ። [፫–፮] በነቢዩ ፡ በኢሳይያስ ፡ ቃል ፡ መጽሐፍ ፦

የጌታን ፡ መንገድ ፡ አዘጋጁ ፡ ጥርጊያውንም ፡ አቅኑ ፡ እያለ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የሚጮኽ ፡ ሰው ፡ ድምፅ ፤ ዐዘቅቱ ፡ ሁሉ ፡ ይሞላ ፡ ተራራውና ፡ ኮረብታውም ፡ ሁሉ ፡ ዝቅ ፡ ይበል ፥ ጠማማውም ፡ የቀና ፡ መንገድ ፡ ይሁን ፥ ሸካራውም ፡ መንገድ ፡ ትክክል ፡ ይሁን ፤ ሥጋም ፡ የለበሰ ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ማዳን ፡ ይይ ፡

ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ለኃጢአት ፡ ስርየት ፡ የንስሐን ፡ ጥምቀት ፡ እየሰበከ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ዙሪያ ፡ ወዳለችው ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ መጣ ።

[፯] ስለዚህ ፡ ከእርሱ ፡ ሊጠመቁ ፡ ለወጡት ፡ ሕዝብ ፡ እንዲህ ፡ ይላቸው ፡ ነበር ፦ እናንተ ፡ የእፉኝት ፡ ልጆች ፥ ከሚመጣው ፡ ቍጣ ፡ እንድትሸሹ ፡ ማን ፡ አመለከታችሁ ? [፰] እንግዲህ ፡ ለንስሐ ፡ የሚገባ ፡ ፍሬ ፡ አድርጉ ፤ በልባችሁም ፦ አብርሃም ፡ አባት ፡ አለን ፡ ማለትን ፡ አትጀምሩ ፤ ከእነዚህ ፡ ድንጋዮች ፡ ለአብርሃም ፡ ልጆች ፡ ሊያስነሣለት ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲችል ፡ እላችኋለሁና ። [፱] አሁንስ ፡ ምሳር ፡ ደግሞ ፡ በዛፎች ፡ ሥር ፡ ተቀምጦአል ፤ እንግዲህ ፡ መልካም ፡ ፍሬ ፡ የማያደርግ ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ይቈረጣል ፡ ወደ ፡ እሳትም ፡ ይጣላል ።

[፲] ሕዝቡም ፦ እንግዲህ ፡ ምን ፡ እናድርግ ? ብለው ፡ ይጠይቁት ፡ ነበር ። [፲፩] መልሶም ፦ ሁለት ፡ ልብስ ፡ ያለው ፡ ለሌለው ፡ ያካፍል ፥ ምግብም ፡ ያለው ፡ እንዲሁ ፡ ያድርግ ፡ ይል ፡ ነበር ። [፲፪] ቀራጮችም ፡ ደግሞ ፡ ሊጠመቁ ፡ መጥተው ፦ መምህር ፡ ሆይ ፥ ምን ፡ እናድርግ ? አሉት ። [፲፫] ከታዘዛችሁ ፡ አብልጣችሁ ፡ አትውሰዱ ፡ አላቸው ። [፲፬] ጭፍሮችም ፡ ደግሞ ፦ እኛ ፡ ደግሞ ፡ ምን ፡ እናድርግ ? ብለው ፡ ይጠይቁት ፡ ነበር ። እርሱም ፦ በማንም ፡ ግፍ ፡ አትሥሩ ፡ ማንንም ፡ በሐሰት ፡ አትክሰሱ ፥ ደመወዛችሁም ፡ ይብቃችሁ ፡ አላቸው ።

[፲፭] ሕዝቡም ፡ ሲጠብቁ ፡ ሳሉ ፡ ሁሉም ፡ በልባቸው ፡ ስለ ፡ ዮሐንስ ፦ ይህ ፡ ክርስቶስ ፡ ይሆንን ? ብለው ፡ ሲያስቡ ፡ ነበር ፥ [፲፮] ዮሐንስ ፡ መልሶ ፦ እኔስ ፡ በውኃ ፡ አጠምቃችኋለሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የጫማውን ፡ ጠፍር ፡ መፍታት ፡ የማይገባኝ ፡ ከእኔ ፡ የሚበረታ ፡ ይመጣል ፤ እርሱ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስና ፡ በእሳት ፡ ያጠምቃችኋል ፤ [፲፯] መንሹም ፡ በእጁ ፡ ነው ፥ አውድማውንም ፡ ፈጽሞ ፡ ያጠራል ፥ ስንዴውንም ፡ በጎተራው ፡ ይከታል ፥ ገለባውን ፡ ግን ፡ በማይጠፋ ፡ እሳት ፡ ያቃጥለዋል ፡ አላቸው ።

[፲፰] ስለዚህ ፡ ሕዝቡን ፡ በብዙ ፡ ሌላ ፡ ምክር ፡ እየመከራቸው ፡ ወንጌልን ፡ ይሰብክላቸው ፡ ነበር ፤ [፲፱] የአራተኛው ፡ ክፍል ፡ ገዥ ፡ ሄሮድስ ፡ ግን ፥ ስለ ፡ ሄሮድያዳ ፡ ስለ ፡ ወንድሙ ፡ ስለ ፡ ፊልጶስ ፡ ሚስትና ፡ ሄሮድስ ፡ ስላደረገው ፡ ሌላ ፡ ክፋት ፡ ሁሉ ፡ ዮሐንስ ፡ ስለ ፡ ገሠጸው ፥ [፳] ይህን ፡ ደግሞ ፡ ከሁሉ ፡ በላይ ፡ ጨምሮ ፡ ዮሐንስን ፡ በወኅኒ ፡ አገባው ።

[፳፩] ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ከተጠመቁ ፡ በኋላ ፡ ኢየሱስ ፡ ደግሞ ፡ ተጠመቀ ። ሲጸልይም ፡ ሰማይ ፡ ተከፈተ ፥ [፳፪] መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ በአካል ፡ መልክ ፡ እንደ ፡ ርግብ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ወረደ ፤ የምወድህ ፡ ልጄ ፡ አንተ ፡ ነህ ፥ በአንተ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ የሚል ፡ ድምፅም ፡ ከሰማይ ፡ መጣ ።

[፳፫] ኢየሱስም ፡ ሊያስተምር ፡ ሲጀምር ፡ ዕድሜው ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ ሆኖት ፡ ነበር ፤ እንደመሰላቸው ፡ የዮሴፍ ፡ ልጅ ፡ ሆኖ ፥ የኤሊ ፡ ልጅ ፥ [፳፬] የማቲ ፡ ልጅ ፥ የሌዊ ፡ ልጅ ፥ የሚልኪ ፡ ልጅ ፥ የዮና ፡ ልጅ ፥ የዮሴፍ ፡ ልጅ ፥ [፳፭] የማታትዩ ፡ ልጅ ፥ የአሞጽ ፡ ልጅ ፥ የናሆም ፡ ልጅ ፥ የኤሲ

፪ ። ፵፯ ፤ ማቴ. ፯፥፳፰ ። ፵፱ ፤ ዮሐ. ፪፥፲፮ ።

፫ ። ፩–፲፯ ፤ ማቴ. ፫፥፩–፲፪ ፤ ማር. ፩፥፩–፰ ። ፬–፮ ፤ ኢሳ. ፵፥፫–፭ ፤ [illegible] ። ፰ ፤ ዮሐ. ፰፥፴፱ ። ፱ ፤ ማቴ. ፯፥፲፱ ። ፲፩ ፤ ኢሳ. ፶፰፥፯ ። ፲፪ ፤ ዮሐ. ፩፥፲፱ ፤ ፳ ። ፲፮ ፤ ዮሐ. ፩፥፳፮ ፤ [illegible] ። ፲፱ ፤ ፳ ፤ ማር. ፮፥፲፯ ። ፳፩ ፤ ፳፪ ፤ ማቴ. ፫፥፲፫–፲፯ ፤ ማር. ፩፥፱–፲፩ ። ፳፪ ፤ መዝ. ፪፥፯ ፤ ዮሐ. ፲፪፥፳፰ ፤ [illegible] ። ፳፫–፴፰ ፤ ማቴ. ፩፥፩–፲፯ ። ፳፫ ፤ መዝ. ፪፥[illegible] ፤ ማቴ. ፲፫፥፶፭ ፤ ዮሐ. ፩፥፵፭ ፤ ፮፥፵፪ ።

፳፮ ሊም ፡ ልጅ፥ የናጌ ፡ ልጅ፥ የማአት ፡ ልጅ፥ የማ
ታትዩ ፡ ልጅ፥ የሴሜይ ፡ ልጅ፥ የዮሴፍ ፡ ልጅ፥
፳፯ የዮዳ ፡ ልጅ፥ የዮናን ፡ ልጅ፥ የሬስ ፡ ልጅ፥ የዘሩ
ባቤል ፡ ልጅ፥ የሰላትያል ፡ ልጅ፥ የኔሪ ፡ ልጅ፥
፳፰ የሚልኪ ፡ ልጅ፥ የሐዲ ፡ ልጅ፥ የዮሳስ ፡ ልጅ፥
የቆሳም ፡ ልጅ፥ የኤልሞዳም ፡ ልጅ፥ የኤር ፡
፳፱ ልጅ፥ የዮሴዕ ፡ ልጅ፥ የኤልዓዘር ፡ ልጅ፥ የዮ
ራም ፡ ልጅ፥ የማጣት ፡ ልጅ፥ የሌዊ ፡ ልጅ፥
፴ የስምዖን ፡ ልጅ፥ የይሁዳ ፡ ልጅ፥ የዮሴፍ ፡ ልጅ፥
፴፩ የዮናን ፡ ልጅ፥ የኤልያቄም ፡ ልጅ፥ የሚልያ ፡
ልጅ፥ የማይናን ፡ ልጅ፥ የማጣት ፡ ልጅ፥ የና
፴፪ ታን ፡ ልጅ፥ የዳዊት ፡ ልጅ፥ የእሴይ ፡ ልጅ፥
የኢዮቤድ ፡ ልጅ፥ የቦዔዝ ፡ ልጅ፥ የሰልሞን ፡
፴፫ ልጅ፥ የነአሶን ፡ ልጅ፥ የአሚናዳብ ፡ ልጅ፥ የአ
ራም ፡ ልጅ፥ የአርኒ ፡ ልጅ፥ የኤስሮም ፡ ልጅ፥
፴፬ የፋሬስ ፡ ልጅ፥ የይሁዳ ፡ ልጅ፥ የያዕቆብ ፡ ልጅ፥
የይስሐቅ ፡ ልጅ፥ የአብርሃም ፡ ልጅ፥ የታራ ፡
፴፭ ልጅ፥ የናኮር ፡ ልጅ፥ የሴሮህ ፡ ልጅ፥ የራጋው ፡
ልጅ፥ የፋሌቅ ፡ ልጅ፥ የአቤር ፡ ልጅ፥ የሳላ ፡
፴፮ ልጅ፥ የቃይንም ፡ ልጅ፥ የአርፋክስድ ፡ ልጅ፥
የሴም ፡ ልጅ፥ የኖኅ ፡ ልጅ፥ የላሜህ ፡ ልጅ፥
፴፯ የማቱሳላ ፡ ልጅ፥ የሄኖክ ፡ ልጅ፥ የያሬድ ፡ ልጅ፥
፴፰ የመላልኤል ፡ ልጅ፥ የቃይናን ፡ ልጅ፥ የሄኖስ ፡
ልጅ፥ የሴት ፡ ልጅ፥ የአዳም ፡ ልጅ፥ የእግዚአ
ብሔር ፡ ልጅ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ኢየሱስም ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ መልቶበት ፡ ከዮ
ርዳኖስ ፡ ተመለሰ፥ በመንፈስም ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡
፪ በዳ ፡ ተመርቶ፥ አርባ ፡ ቀን ፡ ከዲያብሎስ ፡ ተፈ
ተነ ። በነዚያም ፡ ቀኖች ፡ ምንም ፡ አልበላም፥
፫ ከተጨረሱም ፡ በኋላ ፡ ተራበ ። ዲያብሎስም ፦
የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ከሆንህ፥ ይህን ፡ ድን
ጋይ ፡— እንጀራ ፡ ሁን ፡ ብለህ ፡ እዘዝ ፡ አለው ።
፬ ኢየሱስም ፡— ሰው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡
ሁሉ ፡ እንጂ ፡ በእንጀራ ፡ ብቻ ፡ አይኖርም ፡ ተብሎ ፡
፭ ተጽፎአል ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ። ዲያብሎስም ፡
ረጅም ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ተራራ ፡ አውጥቶ ፡ የዓለምን ፡
መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ በቅጽበት ፡ አሳየው ።
፮ ዲያብሎስም ፡— ይህ ፡ ሥልጣን ፡ ሁሉ ፡ ክብራ
ቸውም ፡ ለእኔ ፡ ተሰጥቶአል ፡ ለምወደውም ፡
ለማንም ፡ እሰጠዋለሁና ፡ ለአንተ ፡ እሰጥሃለሁ ፤
፯ ስለዚህ ፡ አንተ ፡ ለእኔ ፡ ፊት ፡ ብትሰግድ፥
፰ ሁሉ ፡ ለአንተ ፡ ይሆናል ፡ አለው ። ኢየሱስም ፡
መልሶ ፡— ለጌታ ፡ ለአምላክህ ፡ ስገድ ፡ እርሱንም ፡
ብቻ ፡ አምልክ ፡ ተብሎ ፡ ተጽፎአል ፡ አለው ።
፱—፲፩ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ደግሞ ፡ ወሰደው ፤ በመቅ
ደስም ፡ ጫፍ ፡ ላይ ፡ አቁሞ ፡—
ይጠብቁህ ፡ ዘንድ ፡ መላእክቱን ፡ ስለ ፡ አንተ ፡
ያዝልሃል፥ እግርህንም ፡ በድንጋይ ፡ ከቶ ፡
እንዳትሰናከል ፡ በእጃቸው ፡ ያነሡሃል ፡
ተብሎ ፡ ተጽፎአልና ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅስ ፡
ከሆንህ፥ ከዚህ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ ራስህን ፡ ወርውር ፡
፲፪ አለው ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡— ጌታን ፡ አምላ
ክህን ፡ አትፈታተነው ፡ ተብሎአል ፡ አለው ።
፲፫ ዲያብሎስም ፡ ፈተናውን ፡ ሁሉ ፡ ከጨረሰ ፡ በኋላ ፡
እስከ ፡ ጊዜው ፡ ከእርሱ ፡ ተለየ ።
፲፬ ኢየሱስም ፡ በመንፈስ ፡ ኃይል ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡
ተመለሰ ፤ ስለ ፡ እርሱም ፡ በዙሪያው ፡ ባሉችው ፡
፲፭ አገር ፡ ሁሉ ፡ ዝና ፡ ወጣ ። እርሱም ፡ በምኩራብ
ቸው ፡ ያስተምር፥ ሁሉም ፡ ያመሰግኑት ፡ ነበር ።
፲፮ ወዳደገበቱም ፡ ወደ ፡ ናዝሬት ፡ መጣ ፤ እንደ ፡
ልማዱም ፡ በሰንበት ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ምኩራብ ፡
፲፯—፲፱ ገባ፥ ሊያነብም ፡ ተነሣ ። የነቢዩንም ፡ የኢሳ
ይያስን ፡ መጽሐፍ ፡ ሰጡት፥ መጽሐፉንም ፡
በተረተረ ፡ ጊዜ ፡—
የጌታ ፡ መንፈስ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ነው፥ ለድ
ሆች ፡ ወንጌልን ፡ እሰብክ ፡ ዘንድ ፡ ቀብቶ
ኛልና ፤ ለታሰሩትም ፡ መፈታትን ፡ ለዕው
ሮችም ፡ ማየትን ፡ እሰብክ ፡ ዘንድ፥ የተጠ
ቁትንም ፡ ነጻ ፡ አወጣ ፡ ዘንድ ፡ የተወደደ
ችውንም ፡ የጌታን ፡ ዓመት ፡ እሰብክ ፡ ዘንድ ፡
ልኮኛል ፡
፳ ተብሎ ፡ የተጻፈበትን ፡ ስፍራ ፡ አገኘ ። መጽሐ
ፉንም ፡ ጠቅልሎ ፡ ለአገልጋዩ ፡ ሰጠውና ፡ ተቀ
መጠ ፤ በምኩራብም ፡ የነበሩት ፡ ሁሉ ፡ ትኩር ፡
፳፩ ብለው ፡ ይመለከቱት ፡ ነበር ። እርሱም ፡— ዛሬ ፡
ይህ ፡ መጽሐፍ ፡ በጆሮአችሁ ፡ ተፈጸመ ፡ ይላ
፳፪ ቸው ፡ ጀመር ። ሁሉም ፡ ይመሰክሩለት ፡ ነበር፥
ከአፉም ፡ ከሚወጣው ፡ ከጸጋው ፡ ቃል ፡ የተ
ነሣ ፡ እየተደነቁ ፡— ይህ ፡ የዮሴፍ ፡ ልጅ ፡ አይ
፳፫ ደለምን ? ይሉ ፡ ነበር ። እርሱም ፡— ያለ ፡ ጥር
ጥር ፡ ይህን ፡ ምሳሌ ፡— ባለ ፡ መድኃኒት ፡ ሆይ፥
ራስህን ፡ ፈውስ ፤ በቅፍርናሆም ፡ እንዳደረግ
ኸው ፡ የሰማነውን ፡ ሁሉ ፡ በዚህ ፡ በገዛ ፡ አገ
ርህ ፡ ደግሞ ፡ አድርግ ፡ ትሉኛላችሁ ፡ አላቸው ።
፳፬ እንዲህም ፡ አለ ፡— እውነት ፡ እላችኋለሁ፥ ነቢይ ፡
፳፭ በገዛ ፡ አገሩ ፡ ከቶ ፡ አይወደድም ። ነገር ፡ ግን ፡
እውነት ፡ እላችኋለሁ፥ በኤልያስ ፡ ዘመን ፡ ሦስት ፡
ዓመት ፡ ከስድስት ፡ ወር ፡ ሰማይ ፡ ተዘግቶ ፡ ሳለ ፡
በምድር ፡ ሁሉ ፡ ብርቱ ፡ ራብ ፡ በነበረ ፡ ጊዜ፥
፳፮ በእስራኤል ፡ ብዙ ፡ መበለቶች ፡ ነበሩ ፤ ኤልያ
ስም ፡ በሲዶና ፡ አገር ፡ ወዳለች ፡ ወደ ፡ ሰራፕታ ፡
ወደ ፡ አንዲት ፡ መበለት ፡ እንጂ ፡ ከእነርሱ ፡
፳፯ ወደ ፡ አንዲቱ ፡ አልተላከም ። በነቢዩ ፡ በኤል
ሳዕ ፡ ዘመንም ፡ በእስራኤል ፡ ብዙ ፡ ለምጻሞች ፡

፫ ። [illegible]

፬ ። [illegible]

ነበሩ ፥ ከዕርያዊው ፡ ከንዕማን ፡ በቀር ፡ ከእነርሱ ፡
፳፰ አንድ ፡ ስንኳ ፡ አልነጻም ። በምኵራብም ፡ የነ
በሩ ፡ ሁሉ ፡ ይህን ፡ ሰምተው ፡ ቍጣ ፡ ሞላባቸው ፥
፳፱ ተነሥተውም ፡ ከከተማ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አወጡት ፥
ይጥሉትም ፡ ዘንድ ፡ ከተማቸው ፡ ተሠርታበት ፡
ወደ ፡ ነበረች ፡ ወደ ፡ ተራራው ፡ አፋፍ ፡ ወሰዱት ፤
፴ እርሱ ፡ ግን ፡ በመካከላቸው ፡ አልፎ ፡ ሄደ ።
፴፩ ወደ ፡ ገሊላ ፡ ከተማም ፡ ወደ ፡ ቅፍርናሆም ፡
ወረደ ። በሰንበትም ፡ ያስተምራቸው ፡ ነበር ፤
፴፪ ቃሉ ፡ በሥልጣን ፡ ነበርና ፡ በትምህርቱ ፡ ተገ
፴፫ ረሙ ። በምኵራብም ፡ የርኵስ ፡ ጋኔን ፡ መን
ፈስ ፡ ያደረበት ፡ ሰው ፡ ነበረ ፥ በታላቅ ፡ ድም
፴፬ ፅም ፡ ጮኾ ፦ ተው ፥ የናዝሬቱ ፡ ኢየሱስ ፡
ሆይ ፥ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አለን ? ልታጠፋን ፡
መጣህን ? ማን ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ አውቄሃለሁ ፥
፴፭ አንተ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቅዱሱ ፡ አለ ። ኢየሱ
ስም ፦ ዝም ፡ በል ፡ ከእርሱም ፡ ውጣ ፡ ብሎ ፡
ገሠጸው ። ጋኔኑም ፡ በመካከላቸው ፡ ጥሎት ፡
፴፮ ሳይጐዳው ፡ ከእርሱ ፡ ወጣ ። ሁሉንም ፡ መደ
ነቅ ፡ ያዛቸው ፥ እርስ ፡ በርሳቸውም ፦ ይህ ፡
ቃል ፡ምንድር ፡ ነው ? በሥልጣንና ፡ በኃይል ፡
ርኵሳን ፡ መናፍስትን ፡ ያዝዛልና ፥ ይወጡማል ፡
፴፯ ብለው ፡ ተነጋገሩ ። ዝናም ፡ በዙሪያው ፡ ባለች ፡
አገር ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ወጣ ።
፴፰ በምኵራብም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ስምዖን ፡ ቤት ፡
ገባ ። የስምዖንም ፡ አማት ፡ በብርቱ ፡ ንዳድ ፡
፴፱ ታማ ፡ ነበር ፡ ስለ ፡ እርስዋም ፡ ለመኑት ። በአጠ
ገብዋም ፡ ቆሞ ፡ ንዳዱን ፡ ገሠጸውና ፡ ለቀቃት ፤
ያንጊዜውንም ፡ ተነሥታ ፡ አገለገለቻቸው ።
፵ ፀሐይም ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ደዌ ፡ የተ
ያዙ ፡ በሽተኞችን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አመጡአ
ቸው ፤ እርሱም ፡ በእያንዳንዳቸው ፡ ላይ ፡ እጁን ፡
፵፩ ጭኖ ፡ ፈወሳቸው ። አጋንንትም ፡ ደግሞ ፦
አንተ ፡ ክርስቶስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነህ ፡
እያሉ ፡ እየጮኹም ፡ ከብዙዎች ፡ ይወጡ ፡ ነበር ፤
ገሠጻቸውም ፡ ክርስቶስም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አውቀ
ውት ፡ ነበርና ፡ እንዲናገሩ ፡ አልፈቀደላቸውም ።
፵፪ በጸበም ፡ ጊዜ ፡ ወጥቶ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
ሄደ ፤ ሕዝቡም ፡ ይፈልጉት ፡ ነበር ፤ ወደ ፡ እር
ሱም ፡ መጡ ፥ ከእነርሱም ፡ ተለይቶ ፡ እንዳይ
፵፫ ሄድ ፡ ሊከለክሉት ፡ ወደዱ ። እርሱ ፡ ግን ፦ ስለ
ዚህ ፡ ተልኬአለሁና ፡ ለሌሎቹ ፡ ከተማዎች ፡
ደግሞ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ ወን
ጌል ፡ እሰብክ ፡ ዘንድ ፡ ይገባኛል ፡ አላቸው ።
፵፬ በገሊላም ፡ ምኵራቦች ፡ ይሰብክ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ሕዝቡም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ እየሰሙ ፡
ሊያስጠብቡት ፡ ሳሉ ፥ እርሱ ፡ ራሱ ፡ በጌንሳሬጥ ፡
ባሕር ፡ ዳር ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፤ በባሕር ፡ ዳርም ፡ ፪
ቆመው ፡ የነበሩትን ፡ ሁለት ፡ ታንኳዎች ፡ አየ ፤
ዓሣ ፡ አጥማጆች ፡ ግን ፡ ከእነርሱ ፡ ውስጥ ፡ ወጥ
ተው ፡ መረባቸውን ፡ ያጥቡ ፡ ነበር ። ከታን ፫
ኳዎቹም ፡ የስምዖን ፡ ወደ ፡ ነበረች ፡ ወደ ፡ አን
ዲቱ ፡ ገብቶ ፡ ከምድር ፡ ጥቂት ፡ ፈቀቅ ፡ እንዲ
ያደርጋት ፡ ለመነው ፤ በታንኳይቱም ፡ ተቀምጦ ፡
ሕዝቡን ፡ ያስተምር ፡ ነበር ። ንግሩንም ፡ ከጨረሰ ፡ ፬
በኋላ ፥ ስምዖንን ፦ ወደ ፡ ጥልቁ ፡ ፈቀቅ ፡ በል ፡
መረባችሁንም ፡ ለማጥመድ ፡ ጣሉ ፡ አለው ።
ስምዖንም ፡ መልሶ ፦ አቤቱ ፥ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ ፭
አድረን ፡ ስንደክም ፡ ምንም ፡ አልያዝንም ፤ ነገር ፡
ግን ፡ በቃልህ ፡ መረቦቹን ፡ እጥላለሁ ፡ አለው ።
ይህንም ፡ ባደረጉ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ዓሣ ፡ ያዙ ፤ ፮
መረባቸውም ፡ ተቀደዱ ። በሌላ ፡ ታንኳም ፡ ፯
የነበሩትን ፡ ጓደኞቻቸውን ፡ መጥተው ፡ እንዲ
ያግዙአቸው ፡ ጠቀሱ ፤ መጥተውም ፡ ሁለቱ ፡
ታንኳዎች ፡ እስኪሰጥሙ ፡ ድረስ ፡ ሞሉአቸው ።
ስምዖን ፡ ጴጥሮስ ፡ ግን ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ በኢየሱስ ፡ ፰
ጕልበት ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ እኔ ፡
ኃጢአተኛ ፡ ነኝና ፡ ከኔ ፡ ተለይ ፡ አለው ። ስላ ፱
ጠመዱት ፡ ዓሣ ፡ እርሱ ፡ ከእርሱ ፡ ጋርም ፡ የነ
በሩ ፡ ሁሉ ፡ ተደንቀዋልና ፤ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ ፲
የስምዖን ፡ ባልንጀሮች ፡ የነበሩ ፡ የዘብዴዎስ ፡
ልጆች ፡ ያዕቆብና ፡ ዮሐንስም ፡ ተደነቁ ። ኢየ
ሱስም ፡ ስምዖንን ፦ አትፍራ ፤ ከእንግዲህ ፡
ወዲህ ፡ ሰውን ፡ የምታጠምድ ፡ ትሆናለህ ፡
አለው ። ታንኳዎችንም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ አድር ፲፩
ሰው ፡ ሁሉን ፡ ትተው ፡ ተከተሉት ።
ከከተማዎችም ፡ በአንዲቱ ፡ ሳለ ፥ እነሆ ፥ ፲፪
ለምጽ ፡ የሞላበት ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ኢየሱስንም ፡
አይቶ ፡ በፊቱ ፡ ወደቀና ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ብትወ
ድስ ፥ ልታነጻኝ ፡ ትችላለህ ፡ ብሎ ፡ ለመነው ።
እጁንም ፡ ዘርግቶ ፡ዳሰሰውና ፦ እወዳለሁ ፥ ፲፫
ንጻ ፡ አለው ፤ ወዲያውም ፡ ለምጹ ፡ለቀቀው ።
እርሱም ፡ ለማንም ፡ እንዳይናገር ፡ አዘዘው ፥ ነገር ፡ ፲፬
ግን ፦ ሄደህ ፡ ራስህን ፡ ለካህን ፡ አሳይ ፥ ለእነር
ሱም ፡ ምስክር ፡ እንዲሆን ፡ ስለ ፡ መንጻትህ ፡
ሙሴ ፡ እንዳዘዘ ፡ መሥዋዕት ፡ አቅርብ ፡ አለው ።
ወሬው ፡ ግን ፡ አብዝቶ ፡ ወጣ ፥ ብዙ ፡ ሕዝብም ፲፭
ሊሰሙትና ፡ ከደዌአቸው ፡ ሊፈወሱ ፡ ይሰበሰቡ ፡
ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ፲፮
ፈቀቅ ፡ ብሎ ፡ ይጸልይ ፡ ነበር ።
አንድ ፡ ቀንም ፡ ያስተምር ፡ ነበር ፤ ከገሊላና ፡ ፲፯
ከይሁዳ ፡ መንደሮችም ፡ ሁሉ ፡ ከኢየሩሳሌምም ፡
መጥተው ፡ የነበሩ ፡ ፈሪሳውያንና ፡ የሕግ ፡ መም
ህራን ፡ ይቀመጡ ፡ ነበር ፤ እርሱም ፡ እንዲፈውስ ፡
የጌታ ፡ ኃይል ፡ ሆነለት ። እነሆም ፥ አንድ ፡ ሽባ ፡ ፲፰
በአልጋ ፡ ተሸክመው ፡ አመጡ ፤ አግብተውም ፡

፬ ። ፴፩ ፡ ዮሐ. ፳ ፥ ፶፱ ፤ ፲ ፥ ፴፱ ። ፴፩—፴፯ ፤ ማቴ. ፬ ፥ ፲፫ ፤ ማር. ፩ ፥ ፳፩—፳፰ ። ፴፪ ፤ ፴፯ ፤ ማቴ. ፯ ፥ ፳፰ ፤ ፳፱ ። ፴፰—፵፩ ፤ ማቴ. ፰ ፥ ፲፬—፲፯ ፤ ማር. ፩ ፥ ፳፱—፴፬ ። ፵፩ ፤ ማቴ. ፰ ፥ ፳፱ ፤ ማር. ፫ ፥ ፲፩ ፤ ዮሐ. ፩ ፥ ፵ ። ፵፪—፵፬ ፤ ማር. ፩ ፥ ፴፭—፴፱ ።

፭ ። ፩—፲፩ ፤ ማቴ. ፬ ፥ ፲፰—፳፪ ፤ ማር. ፩ ፥ ፲፮—፳ ፤ ዮሐ. ፩ ፥ ፵፩—፵፪ ። ፲፩ ፤ ም. ፲፰ ፥ ፳፰ ፤ ማቴ. ፲፱ ፥ ፳፯ ። ፲፪—፲፬ ፤ ማቴ. ፰ ፥ ፪—፬ ፤ ማር. ፩ ፥ ፵—፵፬ ። ፲፬ ፤ ዘሌዋ. ፲፬ ፥ ፪—፴፪ ። ፲፭ ፤ ም. ፮ ፥ ፲፪ ፤ ፱ ፥ ፲፰ ፤ ፳፰ ፤ ፲፮ ፥ ፩ ፤ ማቴ. ፲፬ ፥ ፳፫ ፤ ማር. ፩ ፥ ፴፭ ። ፲፰—፳፮ ፤ ማቴ. ፱ ፥ ፪—፰ ፤ ማር. ፪ ፥ ፫—፲፪ ።

፲፱ በፊቱ ፡ ሊያኖሩት ፡ ይሹ ፡ ነበር ። ስለ ፡ ሕዝቡም ፡ ብዛት ፡ እንዴት ፡ አድርገው ፡ እንዲያገቡት ፡ ሊያ ቅታቸው ፥ ወደ ፡ ሰገነቱ ፡ ወጡ ፡ የጣራውንም ፡ ጡብ ፡ አሳልፈው ፡ በመካከል ፡ በኢየሱስ ፡ ፊት ፡ ፳ ከነአልጋው ፡ አወረዱት ። እምነታቸውንም ፡ አይቶ ፦ አንተ ፡ ሰው ፥ ኃጢአትህ ፡ ተሰረየች ፳፩ ልህ ፡ አለው ። ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያንም ፦ ይህ ፡ የሚሳደብ ፡ ማን ፡ ነው ? ከአንዱ ፡ ከእግዚአብ ሔር ፡ በቀር ፡ ኃጢአት ፡ ሊያስተሰርይ ፡ ማን ፡ ፳፪ ይችላል ? ብለው ፡ ያስቡ ፡ ጀመር ። ኢየሱስም ፡ አሳባቸውን ፡ እያወቀ ፡ መልሶ ፦ በልባችሁ ፡ ፳፫ ምን ፡ ታስባላችሁ ? ኃጢአትህ ፡ ተሰረየችልህ ፡ ከማለት ፡ ወይስ ፦ ተነሣና ፡ ሂድ ፡ ከማለት ፡ ማና ፳፬ ቸው ፡ ይቀላል ? ነገር ፡ ግን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ኃጢአት ፡ ሊያስተሰርይ ፡ ለሰው ፡ ልጅ ፡ ሥልጣን ፡ እንዳለው ፡ እንድታውቁ ፡ ብሎ ፥ ሽባውን ፦ አንተን ፡ እልሃለሁ ፥ ተነሣ ፥ አልጋህን ፡ ተሸ ፳፭ ክመህ ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ ሂድ ፡ አለው ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ በፊታቸው ፡ ተነሣ ፥ ተኝቶበትም ፡ የነ በረውን ፡ ተሸክሞ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እያመሰ ፳፮ ገነ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ። ሁሉንም ፡ መገረም ፡ ያዛቸው ፥ እግዚአብሔርንም ፡ አመሰግነው ፦ ዛሬስ ፡ ድንቅ ፡ ነገር ፡ አየን ፡ እያሉ ፡ ፍርሃት ፡ ሞላባቸው ።

፳፯ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወጥቶ ፡ ሌዊ ፡ የሚባል ፡ ቀራጭ ፡ በመቅረጫው ፡ ተቀምጦ ፡ ተመለከ ፳፰ ተና ፦ ተከተለኝ ፡ አለው ። ሁሉንም ፡ ተወ ፤ ተነሥቶም ፡ ተከተለው ።

፳፱ ሌዊም ፡ በቤቱ ፡ ታላቅ ፡ ግብዣ ፡ አደረገለት ፤ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ በማዕድ ፡ ተቀምጠው ፡ የነበሩ ፡ ከቀራጮችና ፡ ከሌሎች ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ፴ ነበሩ ። ፈሪሳውያንና ፡ ጻፎቻቸውም ፡ በደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ላይ ፦ ስለ ፡ ምን ፡ ከቀራጮችና ፡ ከኃጢአተኞች ፡ ጋር ፡ ትበላላችሁ ፡ ትጠጡማ ፴፩ ላችሁ ? ብለው ፡ አንጐራጐሩ ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፦ ሕመምተኞች ፡ እንጂ ፡ ባለ ፡ ጤና ዎች ፡ ባለ ፡ መድኃኒት ፡ አያስፈልጋቸውም ፤ ፴፪ ኃጢአተኞችን ፡ ወደ ፡ ንስሐ ፡ እንጂ ፡ ጻድቃ ንን ፡ ልጠራ ፡ አልመጣሁም ፡ አላቸው ።

፴፫ እነርሱም ፦ የዮሐንስ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ብዙ ፡ ይጦማሉ ፡ ጸሎትስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ያደርጋሉ ፥ ደግሞም ፡ የፈሪሳውያን ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እንደዚሁ ፡ ያደ ርጋሉ ፤ የአንተ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ግን ፡ ይበ ፴፬ ላሉ ፡ ይጠጣሉም ? አሉት ። ኢየሱስም ፦ ሙሽራው ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ሳለ ፡ ሚዜዎችን ፡ ፴፭ ልታስጦሙ ፡ ትችላላችሁን ? ነገር ፡ ግን ፡ ወራት ፡ ይመጣል ፥ ሙሽራውም ፡ ከእነርሱ ፡ ሲወሰድ ፡ ያንጊዜ ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ ይጦማሉ ፡ አላቸው ።

፴፮ ደግሞም ፡ ምሳሌ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ነገራቸው ፦ የአዲስ ፡ ልብስ ፡ እራፊ ፡ በረጅ ፡ ልብስ ፡ ላይ ፡ የሚያኖር ፡ የለም ፤ ቢደረግ ፡ ግን ፡ አዲሱን ፡ ይቀ ደዋል ፡ ደግሞም ፡ አዲስ ፡ እራፊ ፡ ለአሮጌው ፡ ፴፯ አይስማማውም ። በረጅ ፡ አቁማዳም ፡ አዲስ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ የሚያኖር ፡ የለም ፤ ቢደረግ ፡ ግን ፡ አዲሱ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ አቁማዳውን ፡ ያፈ ነዳል ፥ እርሱም ፡ ይፈስሳል ፡ አቁማዳውም ፡ ይጠ ፴፰ ፋል ። አዲሱን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ግን ፡ በአዲስ ፡ አቁማዳ ፡ ማኖር ፡ ይገባል ፥ ሁለቱም ፡ ይጠባበ ፴፱ ቃሉ ። አሮጌ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ሲጠጣ ፡ አዲሱን ፡ የሚሻ ፡ ማንም ፡ የለም ፤ አሮጌው ፡ ይጣፍጣል ፡ ይላልና ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ በሰንበትም ፡ በእርሻ ፡ መካከል ፡ ያልፍ ፡ ነበር ፤ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ እሸት ፡ ይቀጥፉ ፡ በእጃቸ ፪ ውም ፡ እያሹ ፡ ይበሉ ፡ ነበር ። ከፈሪሳውያን ፡ ግን ፡ አንዳንዶቹ ፦ በሰንበት ፡ ሊደረግ ፡ ያልተ ፈቀደውን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ታደርጋላችሁ ? አሉአ ፫ ቸው ። ኢየሱስም ፡ ለእነርሱ ፡ መልሶ ፦ ዳዊት ፡ በተራበ ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ አብረውት ፡ ከነበሩ ፡ ጋር ፡ ፬ ያደረገውን ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ገባ ፡ ከካህናት ፡ ብቻ ፡ በቀር ፡ መብላት ፡ ያልተ ፈቀደውን ፡ የመሥዋዕትን ፡ እንጀራ ፡ ይዞ ፡ እንደ ፡ በላ ፥ ከእርሱም ፡ ጋር ፡ ለነበሩት ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ሰጣቸው ፡ ይህን ፡ አላነበባችሁምን ? ፭ አለ ። የሰው ፡ ልጅ ፡ የሰንበት ፡ ጌታ ፡ ነው ፡ አላ ቸውም ።

፮ በሌላው ፡ ሰንበትም ፡ ወደ ፡ ምኩራብ ፡ ገብቶ ፡ አስተማረ ፤ በዚያም ፡ ቀኝ ፡ እጁ ፡ የሰለለች ፡ ፯ ሰው ፡ ነበረ ፤ ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያንም ፡ መክሰሻ ፡ ሊያገኙበት ፡ በሰንበት ፡ ይፈውስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፰ ይጠባበቁት ፡ ነበር ። እርሱ ፡ ግን ፡ አሳባቸውን ፡ አውቆ ፡ እጁ ፡ የሰለለችውን ፡ ሰው ፦ ተነሣና ፡ በመካከል ፡ ቁም ፡ አለው ፤ ተነሥቶም ፡ ቆመ ። ፱ ኢየሱስም ፦ እጠይቃችኋለሁ ፤ በሰንበት ፡ በጎ ፡ ማድረግ ፡ ተፈቅዶአልን ፡ ወይስ ፡ ክፉ ? ነፍስ ፡ ፲ ማዳንን ፡ ወይስ ፡ መግደል ? አላቸው ። ሁላቸ ውንም ፡ ዙሪያውን ፡ አየና ፡ ሰውዬውን ፦ እጅ ህን ፡ ዘርጋ ፡ አለው ። እርሱም ፡ እንዲህ ፡ አደ ፲፩ ረገ ፥ እጁም ፡ እንደ ፡ ሁለተኛይቱ ፡ ዳነች ። እነ ርሱም ፡ ቍጣ ፡ ሞላባቸው ፥ በኢየሱስም ፡ ምን ፡ እንዲያደርጉበት ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተነጋገሩ ።

፲፪ በነዚህም ፡ ወራት ፡ ይጸልይ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ተራራ ፡ ወጣ ፥ ሌሊቱንም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እግዚ ፲፫ አብሔር ፡ ሲጸልይ ፡ አደረ ። በነጋም ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ ጠራ ፥ ከእነርሱም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ መረጠ ፡ ደግሞም ፡ ሐዋርያት ፡ ብሎ ፡ ፲፬ ሰየማቸው ፤ እነርሱም ፥ ጴጥሮስ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ የሰየመው ፡ ስምዖን ፥ ወንድሙም ፡ እንድ

፭። ፳፤ ምዕ. ፯፥፵፰። ፳፩፤ ምዕ. ፯፥፵፱፤ ኢሳ. ፵፫፥፳፭። ፳፯—፴፪፤ ማቴ. ፱፥፱—፲፫፤ ማር. ፪፥፲፬—፲፯።

፮። ፩—፭፤ ማቴ. ፲፪፥፩—፰፤ ማር. ፪፥፳፫—፳፰፤ ዘዳግ. ፳፫፥፳፭። ፫፤ ፩ሳሙ. ፳፩፥፮። ፬፤ ዘሌዋ. ፳፬፥፭—፱። ፮—፲፩፤ ማቴ. ፲፪፥፱—፲፬፤ ማር. ፫፥፩—፮። ፯፤ ምዕ. ፲፬፥፩፤ ፫፥፫። ፲፪፤ ምዕ. ፭፥፲፮። ፲፫—፲፮፤ ማቴ. ፲፥፪—፬፤ ማር. ፫፥፲፫—፲፱፤ የሐዋ. ፩፥፲፫።

ርያስ ÷ ያዕቆብም ፡ ዮሐንስም ÷ ፊልጶስም ፡ በር
፲፭ ተሎሜዎስም ÷ ማቴዎስም ፡ ቶማስም ÷ የእልፍ
ዮስ ፡ ልጅ ፡ ያዕቆብም ፡ ቀናተኛ ፡ የሚባለው ፡
፲፮ ስምዖንም ÷ የያዕቆብ ፡ ይሁዳም ÷ አሳልፎ ፡ የሰ
ጠውም ፡ የአስቆሮቱ ፡ ይሁዳ ፡ ናቸው ።

፲፯ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ወርዶ ፡ በተካከለ ፡ ስፍራ ፡
ቆመ ÷ ከደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ወገን ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡
ነበረ ÷ ደግሞም ፡ ሊሰሙትና ፡ ከደዌአቸው ፡
ሊፈወሱ ፡ ከይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ ከኢየሩሳሌምም ፡
ከጢሮስና ፡ ከሲዶና ፡ ባሕር ፡ ዳርም ፡ የመጡ ፡
፲፰ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ ከርኵሳንም ፡ መናፍስት ፡
፲፱ ይማቀቁ ፡ የነበሩት ፡ ተፈወሱ ፤ ከእርሱም ፡
ኃይል ፡ ወጥቶ ፡ ሁሉን ፡ ይፈውስ ፡ ነበርና ፡
ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ሊዳስሱት ፡ ይሹ ፡ ነበር ።

፳ እርሱም ፡ ወደ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ዓይኑን ፡
አንሥቶ ፡ እንዲህም ፡ አላቸው ፡—

እናንተ ፡ ድሆች ፡ ብፁዓን ፡ ናችሁ ÷ የእግዚ
አብሔር ፡ መንግሥት ፡ የእናንተ ፡ ነውና ።

፳፩ እናንተ ፡ አሁን ፡ የምትራቡ ፡ ብፁዓን ፡ ናችሁ ÷
ትጠግባላችሁና ።

እናንተ ፡ አሁን ፡ የምታለቅሱ ፡ ብፁዓን ፡ ናችሁ ÷
ትስቃላችሁና ።

፳፪ ሰዎች ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ልጅ ፡ ሲጠሉአችሁ ፡ ሲለ
ዩአችሁም ፡ ሲነቅፉአችሁም ፡ ስማችሁንም ፡
እንደ ፡ ክፉ ፡ ሲያወጡ ÷ ብፁዓን ፡ ናችሁ ።
፳፫ እነሆ ÷ ዋጋችሁ ፡ በሰማይ ፡ ታላቅ ፡ ነውና ፡ በዚ
ያን ፡ ቀን ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ዝለሉም ፤ አባቶ
ቻቸው ፡ ነቢያትን ፡ እንዲሁ ፡ ያደርጉባቸው ፡
ነበርና ።

፳፬ ነገር ፡ ግን ፡ እናንተ ፡ ባለ ፡ ጠጎች ፡ ወዮላ
ችሁ ÷ መጽናናታችሁን ፡ ተቀብላችኋልና ።

፳፭ እናንተ ፡ አሁን ፡ የጠገባችሁ ፡ ወዮላችሁ ÷
ትራባላችሁና ።

እናንተ ፡ አሁን ፡ የምትስቁ ፡ ወዮላችሁ ÷ ታዝ
ናላችሁና ፡ ታለቅሱማላችሁ ።

፳፮ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ መልካም ፡ ሲናገሩላችሁ ÷ ወዮ
ላችሁ ፤ አባቶቻቸው ፡ ለሐሰተኞች ፡ ነቢያት ፡
እንዲሁ ፡ ያደርጉላቸው ፡ ነበርና ።

፳፯ ነገር ፡ ግን ፡ ለእናንተ ፡ ለምትሰሙ ፡ እላችኋ
ለሁ ÷ ጠላቶቻችሁን ፡ ውደዱ ÷ ለሚጠሉአች
፳፰ ሁም ፡ መልካም ፡ አድርጉ ÷ የሚረግሙአችሁ
ንም ፡ መርቁ ÷ ስለሚበድሉአችሁም ፡ ጸልዩ ።
፳፱ ጕንጭህን ፡ ለሚመታህ ፡ ደግሞ ፡ ሁለተኛውን ፡
ስጠው ÷ መጐናጸፊያህንም ፡ ለሚወስድ ፡ እጀ ፡
፴ ጠባብህን ፡ ደግሞ ፡ አትከልክለው ። ለሚለም
ንህ ፡ ሁሉ ፡ ስጥ ÷ ገንዘብህንም ፡ የሚወስድ ፡ እን
፴፩ ዲመልስ ፡ አትጠይቀው ። ሰዎችም ፡ ሊያደር
ጉላችሁ ፡ እንደምትወዱ ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ እን
ዲሁ ፡ አድርጉላቸው ።

፴፪ የሚወዱአችሁንማ ፡ ብትወዱ ÷ ምን ፡ ምስ
ጋና ፡ አላችሁ ? ኃጢአተኞች ፡ ደግሞ ፡ የሚወ
፴፫ ዱአቸውን ፡ ይወዳሉና ። መልካምም ፡ ለሚያ
ደርጉላችሁ ፡ መልካም ፡ ብታደርጉ ÷ ምን ፡ ምስ
ጋና ፡ አላችሁ ? ኃጢአተኞች ፡ ደግሞ ፡ ያን ፡
፴፬ ያደርጋሉና ። እንድትወስዱባቸው ፡ ተስፋ ፡ ለም
ታደርጉአቸው ፡ ብታበድሩ ÷ ምን ፡ ምስጋና ፡
አላችሁ ? ኃጢአተኞች ፡ ደግሞ ፡ በትክክል ፡ እን
፴፭ ዲቀበሉ ፡ ለኃጢአተኞች ፡ ያበድራሉ ። ነገር ፡
ግን ፡ ጠላቶቻችሁን ፡ ውደዱ ፤ መልካም ፡ አድ
ርጉ ፤ ምንም ፡ ተስፋ ፡ ሳታደርጉም ፡ አበድሩ ÷
ዋጋችሁም ፡ ታላቅ ፡ ይሆናል ÷ የልዑልም ፡
ልጆች ፡ ትሆናላችሁ ÷ እርሱ ፡ ለማያመሰግኑ ፡
፴፮ ለክፉዎችም ፡ ቸር ፡ ነውና ። አባታችሁ ፡ ርኅ
ሩኅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ርኅሩኆች ፡ ሁኑ ።

፴፯ አትፍረዱ ፡ አይፈረድባችሁምም ፤ አትኰ
ንኑ ፡ አትኰነኑምም ። ይቅር ፡ በሉ ፡ ይቅርም ፡
፴፰ ትባላላችሁ ። ስጡ ፡ ይሰጣችሁማል ፤ በምት
ሰፍሩበት ፡ መስፈሪያ ፡ ተመልሶ ፡ ይሰፈርላችኋ
ልና ÷ የተጨቈነና ፡ የተነቀነቀ ፡ የተትረፈረፈም ፡
መልካም ፡ መስፈሪያ ፡ በእቅፋችሁ ፡ ይሰጣች
ኋል ።

፴፱ ምሳሌም ፡ አላቸው ፡— ዕውር ፡ ዕውርን ፡
ሊመራ ፡ ይችላልን ? ሁለቱ ፡ በጕድጓድ ፡ አይወ
፵ ድቁምን ? ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ከመምህሩ ፡ አይበ
ልጥም ፤ ፈጽሞ ፡ የተማረ ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ እንደ ፡
፵፩ መምህሩ ፡ ይሆናል ። በወንድምህም ፡ ዓይን ፡
ያለውን ፡ ጕድፍ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ታያለህ ÷ በራስህ ፡
ዓይን ፡ ግን ፡ ያለውን ፡ ምሰሶ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አት
፵፪ መለከትም ? በዓይንህ ፡ ያለውን ፡ ምሰሶ ፡ ራስህ ፡
ሳታይ ÷ እንዴት ፡ ወንድምህን ፡— ወንድሜ ፡
ሆይ ÷ በዓይንህ ፡ ያለውን ፡ ጕድፍ ፡ ላውጣ ፡ ፍቀ
ድልኝ ፡ ልትል ፡ ትችላለህ ? አንተ ፡ ግብዝ ÷
አስቀድመህ ፡ ከዓይንህ ፡ ምሰሶውን ፡ አውጣ ÷
ከዚያም ፡ በኋላ ፡ በወንድምህ ፡ ዓይን ፡ ያለውን ፡
ጕድፍ ፡ ታወጣ ፡ ዘንድ ፡ አጥርተህ ፡ ታያለህ ።

፵፫ ክፉ ፡ ፍሬ ፡ የሚያደርግ ፡ መልካም ፡ ዛፍ ፡ የለ
ምና ÷ እንዲሁም ፡ መልካም ፡ ፍሬ ፡ የሚያደርግ ፡
፵፬ ክፉ ፡ ዛፍ ፡ የለም ። ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ከፍሬው ፡ ይታ
ወቃልና ፤ ከእሾህ ፡ በለስ ፡ አይለቅሙም ÷ ከእ
ጣጥ ፡ ቍጥቋጦም ፡ ወይን ፡ አይቈርጡም ።
፵፭ በልብ ፡ ሞልቶ ፡ ከተረፈው ፡ አፉ ፡ ይናገራልና ፡
መልካም ፡ ሰው ፡ ከልብ ፡ መልካም ፡ መዝገብ ፡
መልካሙን ፡ ያወጣል ÷ ክፉ ፡ ሰውም ፡ ከልብ ፡
ክፉ ፡ መዝገብ ፡ ክፉውን ፡ ያወጣል ።

፵፮ ስለ ፡ ምን ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ ጌታ ፡ ሆይ ÷ ትሉኛላ
፵፯ ችሁ ÷ የምለውንም ፡ አታደርጉም ? ወደ ፡ እኔ ፡

፮ ። [illegible]

የሚመጣ ፡ ሁሉ ፡ ቃሌንም ፡ ሰምቶ ፡ የሚያደ ርገው ፥ ማንን ፡ እንዲመስል ፡ አሳያችኋለሁ ። ፵፰ ቤት ፡ ሊሠራ ፡ አጥልቆ ፡ የቈፈረ ፡ በዓለት ፡ ላይም ፡ የመሠረተ ፡ ሰውን ፡ ይመስላል ፤ ጐርፍም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ወንዙ ፡ ያን ፡ ቤት ፡ ገፋው ፥ በዓ ለት ፡ ላይም ፡ ስለ ፡ ተመሠረተ ፡ ሊያናውጠው ፡ ፵፱ አልቻለም ። ሰምቶ ፡ የማያደርገው ፡ ግን ፡ ያለ ፡ መሠረት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ቤቱን ፡ የሠራ ፡ ሰውን ፡ ይመስላል ፤ ወንዙም ፡ ገፋው ፡ ወዲያውም ፡ ወደቀ ፡ የዚያ ፡ ቤት ፡ አወዳደቅም ፡ ታላቅ ፡ ሆነ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ቃሉን ፡ ሁሉ ፡ ለሕዝብ ፡ ጆሮዎች ፡ በጨረሰ ፡ ፪ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ቅፍርናሆም ፡ ገባ ። አንድ ፡ የመቶ ፡ አለቃም ፡ ነበረ ፤ የሚወደውም ፡ ባሪያው ፡ ታሞ ፡ ፫ ሊሞት ፡ ቀርቦ ፡ ነበር ። ስለ ፡ ኢየሱስም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ የአይሁድን ፡ ሽማግሎች ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ላከና ፡ መጥቶ ፡ ባሪያውን ፡ እንዲያድን ፡ ለመ ፬ ነው ። እነርሱም ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡ መጥተው ፡— ፭ ይህን ፡ ልታደርግለት ፡ ይገባዋል ፤ ሕዝባችንን ፡ ይወዳልና ፡ ምኵራብም ፡ ራሱ ፡ ሠርቶልናል ፡ ፮ ብለው ፡ አጽንተው ፡ ለመኑት ። ኢየሱስም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ሄደ ። አሁንም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፡ የመቶው ፡ አለቃ ፡ ወዳጆቹን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ላከ ፤ አለውም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ በቤቴ ፡ ጣራ ፡ በታች ፡ ልትገባ ፡ አይገባኝምና ፡ ፯ አትድከም ፤ ስለዚህም ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ልመጣ ፡ እንዲገባኝ ፡ ሰውነቴን ፡ አልቈጠርሁትም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ቃል ፡ ተናገር ፥ ብላቴናዬም ፡ ይፈወ ፰ ሳል ። እኔ ፡ ደግሞ ፡ ከሌሎች ፡ በታች ፡ የም ገዛ ፡ ሰው ፡ ነኝ ፥ ከእኔም ፡ በታች ፡ ወታደ ሮች ፡ አሉኝ ፥ አንዱንም ፡— ሂድ ፡ ብለው ፡ ይሄዳል ፥ ሌላውንም ፡— ና ፡ ብለው ፡ ይመጣል ፥ ባሪያዬንም ፡— ይህን ፡ አድርግ ፡ ብለው ፡ ያደር ፱ ጋል ። ኢየሱስም ፡ ይህን ፡ ሰምቶ ፡ በእርሱ ፡ ተደ ነቀ ፥ ዞወርም ፡ ብሎ ፡ ለተከተሉት ፡ ሕዝብ ፡— እላችኋለሁ ፥ በእስራኤልስ ፡ እንኳ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ትልቅ ፡ እምነት ፡ አላገኘሁም ፡ አላቸው ። ፲ የተላኩትም ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ተመልሰው ፡ ባሪያ ውን ፡ ባለ ፡ ጤና ፡ ሆኖ ፡ አገኙት ።

፲፩ በነገውም ፡ ናይን ፡ ወደምትባል ፡ ወደ ፡ አንዲት ፡ ከተማ ፡ ሄደ ፥ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ብዙ ፡ ሕዝብም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አብረው ፡ ሄዱ ። ፲፪ ወደ ፡ ከተማይቱም ፡ በር ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፥ እነሆ ፥ የሞተ ፡ ሰው ፡ ተሸክመው ፡ አወጡ ፤ እርሱም ፡ ለእናቱ ፡ አንድ ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፥ እር ስዋም ፡ መበለት ፡ ነበረች ፥ ብዙም ፡ የከተማ ፡ ሕዝብ ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ አብረው ፡ ነበሩ ። ፲፫ ጌታም ፡ ባያት ፡ ጊዜ ፡ አዘነላትና ፡— አታልቅሺ ፡ ፲፬ አላት ። ቀርቦም ፡ ቃሬዛውን ፡ ነካ ፥ የተሸከ ሙትም ፡ ቆሙ ፤ አለውም ፡— አንተ ፡ ጐበዝ ፥ ፲፭ እልሃለሁ ፥ ተነሣ ። የሞተውም ፡ ቀና ፡ ብሎ ፡ ተቀመጠ ፡ ሊናገርም ፡ ጀመረ ፥ ለእናቱም ፡ ሰጣት ። ፲፮ ሁሉንም ፡ ፍርሃት ፡ ያዛቸውና ፡— ታላቅ ፡ ነቢይ ፡ በእኛ ፡ መካከል ፡ ተነሥቶአል ፥ ደግሞ ፡— እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ ጐበኘ ፡ እያሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰገኑ ። ፲፯ ይህም ፡ ዝና ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ በይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ በዙሪያውም ፡ ባለች ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ወጣ ።

፲፰ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ለዮሐንስ ፡ እነዚህን ፡ ፲፱ ሁሉ ፡ አወሩ ። ዮሐንስም ፡ ከደቀ ፡ መዛሙ ርቱ ፡ ሁለት ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ጠርቶ ፡— የሚመ ጣው ፡ አንተ ፡ ነህን ፡ ወይስ ፡ ሌላውን ፡ እንጠ ብቅ ? ብሎ ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡ ላከ ። ፳ ሰዎቹም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጥተው ፡— መጥምቁ ፡ ዮሐ ንስ ፡— የሚመጣው ፡ አንተ ፡ ነህን ፡ ወይስ ፡ ሌላ ውን ፡ እንጠብቅ ? ብሎ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ላከን ፡ ፳፩ አሉት ። በዚያች ፡ ሰዓት ፡ ከደዌና ፡ ከሥቃይ ፡ ከክፉዎች ፡ መናፍስትም ፡ ብዙዎችን ፡ ፈወሰ ፥ ፳፪ ለብዙ ፡ ዕውሮችም ፡ ማየትን ፡ ሰጠ ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡— ሄዳችሁ ፡ ያያችሁትን ፡ የሰማችሁት ንም ፡ ለዮሐንስ ፡ አውሩለት ፤ ዕውሮች ፡ ያያሉ ፥ አንካሶችም ፡ ይሄዳሉ ፥ ለምጻሞችም ፡ ይነጻሉ ፥ ደንቆሮዎችም ፡ ይሰማሉ ፥ ሙታንም ፡ ይነሣሉ ፥ ፳፫ ለድሆችም ፡ ወንጌል ፡ ይሰበካል ፤ በእኔም ፡ የማይሰናከለው ፡ ሁሉ ፡ ብፁዕ ፡ ነው ፡ አላቸው ።

፳፬ የዮሐንስ ፡ መልእክተኞችም ፡ ከሄዱ ፡ በኋላ ፥ ለሕዝቡ ፡ ስለ ፡ ዮሐንስ ፡ ይናገር ፡ ጀመር ፡ እን ዲህም ፡ አለ ፡— ምን ፡ ልታዩ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወጣችሁ ? ነፋስ ፡ የሚወዘውዘውን ፡ ሸም ፳፭ በቆን ? ወይስ ፡ ምን ፡ ልታዩ ፡ ወጣችሁ ? ቀጭን ፡ልብስ ፡ የለበሰውን ፡ ሰውን ? እነሆ ፥ ጌጠኛ ፡ ልብስ ፡ የሚለብሱና ፡ በቅምጥልነት ፡ ፳፮ የሚኖሩ ፡ በነገሥታት ፡ ቤት ፡ አሉ ። ወይስ ፡ ምን ፡ ልታዩ ፡ ወጣችሁ ? ነቢይን ? አዎን ፡ እላችኋለሁ ፥ ከነቢይም ፡ የሚበልጠውን ።

፳፯ እነሆ ፥ መንገድህን ፡ በፊትህ ፡ የሚጠርግ ፡
መልእክተኛዬን ፡ በፊትህ ፡ እልካለሁ ፡

ተብሎ ፡ የተጻፈለት ፡ ይህ ፡ ነው ። ፳፰ እላችኋ ለሁ ፥ ከሴቶች ፡ ከተወለዱት ፡ መካከል ፡ ከመ ጥምቁ ፡ ዮሐንስ ፡ የሚበልጥ ፡ ማንም ፡ የለም ፤ በእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ግን ፡ ከሁሉ ፡ የሚ ያንሰው ፡ ይበልጠዋል ። ፳፱ የሰሙትም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ቀራጮች ፡ እንኳ ፡ ሳይቀሩ ፡ በዮሐንስ ፡ ጥምቀት ፡ ተጠምቀው ፡ እግዚአብሔርን ፡ አጸ ፴ ደቁ ፤ ፈሪሳውያንና ፡ ሕግ ፡ አዋቂዎች ፡ ግን ፡ በእርሱ ፡ ስለ ፡ አልተጠመቁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ምክር ፡ ከራሳቸው ፡ ጣሉ ።

፴፩ እንግዲህ ፡ የዚችን ፡ ትውልድ ፡ ሰዎች ፡ በምን ፡ ፴፪ አስመስላቸዋለሁ ? ማንንስ ፡ ይመስላሉ ? በገ በያ ፡ የሚቀመጡትን ፡ ልጆች ፡ ይመስላሉ ፥ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ እየተጠሩ ፡— እንቢልታ ፡ ነፋንላችሁ ፡ አልዘፈናችሁምም ፤ ሙሾ ፡ አወ ፴፫ ጣንላችሁ ፡ አላለቀሳችሁምም ፡ ይላሉ ። መጥ

፯ ። ፩—፲ ፡ ማቴ. ፰ ፡ ፭—፲፫ ። ፲፰ ፡ ምዕ. ፭ ፡ ፴፫ ፤ ዮሐ. ፲፰ ፡ ፲፯ ። ፲፰—፴፭ ፡ ማቴ. ፲፩ ፡ ፪—፲፱ ። ፳፪ ፡ ኢሳ. ፷፩ ፡ ፩ ። ፳፯ ፡ ሚል. ፫ ፡ ፩ ። ፴፱ ፡ ማቴ. ፳፮ ፡ ፮ ።

ምቁ ፡ ዮሐንስ ፡ እንጀራ ፡ ሳይበላ ፡ የወይን ፡
ጠጅም ፡ ሳይጠጣ ፡ መጥቶ ፡ ነበርና ፡— ጋኔን ፡
፴፬ ፡ አለበት ፡ አላችሁት ። የሰው ፡ ልጅ ፡ እየበላና ፡
እየጠጣ ፡ መጥቶአልና ፡— እነሆ ፥ በላተኛና ፡
የወይን ፡ ጠጅ ፡ ጠጭ ፥ የቀራጮችና ፡ የኃጢ
፴፭ ፡ አተኞች ፡ ወዳጅ ፡ አላችሁት ። ጥበብም ፡ ስል
ጆችዋ ፡ ሁሉ ፡ ጸደቀች ።

፴፮ ፡ ከፈሪሳውያንም ፡ አንድ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይበላ ፡
ዘንድ ፡ ለመነው ፤ በፈሪሳዊው ፡ ቤትም ፡ ገብቶ ፡
፴፯ ፡ በማዕድ ፡ ተቀመጠ ። እነሆም ፡ በዚያች ፡ ከተማ ፡
ኃጢአተኛ ፡ የነበረች ፡ አንዲት ፡ ሴት ፤ በፈሪሰ
ዊው ፡ ቤት ፡ በማዕድ ፡ እንደ ፡ ተቀመጠ ፡ በወ
ቀች ፡ ጊዜ ፥ ሽቱ ፡ የሞላበት ፡ የአልባስጥሮስ ፡
፴፰ ፡ ቢልቃጥ ፡ አመጣች ። በስተ ፡ ኋላውም ፡ በእ
ግሩ ፡ አጠገብ ፡ ቆማ ፡ እያለቀሰች ፡ በእንባዋ ፡ እግ
ሩን ፡ ታርስ ፡ ጀመረች ፥ በራስ ፡ ጠጕርዋም ፡ ታብ
ሰው ፡ እግሩንም ፡ ትስመው ፡ ሽቱም ፡ ትቀባው ፡
፴፱ ፡ ነበረች ። የጠራው ፡ ፈሪሳዊም ፡ አይቶ ፡—
ይህስ ፡ ነቢይ ፡ ቢሆን ፥ ይህች ፡ የምትዳስሰው ፡
ሴት ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ እንዴትስ ፡ እንደ ፡ ነበ
ረች ፡ ባወቀ ፡ ነበር ፥ ኃጢአተኛ ፡ ናትና ፡ ብሎ ፡
፵ ፡ በልቡ ፡ አሰበ ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡— ስም
ዖን ፡ ሆይ ፥ የምነግርህ ፡ ነገር ፡ አለኝ ፡ አለው ።
እርሱም ፡— መምህር ፡ ሆይ ፥ ተናገር ፡ አለ ።
፵፩ ፡ ለአንድ ፡ አበዳሪ ፡ ሁለት ፡ ተበዳሪዎች ፡ ነበሩት ፤
በአንዱ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ዲናር ፡ ነበረበት ፡ በሁ
፵፪ ፡ ለተኛውም ፡ አምሳ ። የሚከፍሉትም ፡ ቢያጡ ፡
ለሁለቱም ፡ ተወላቸው ። እንግዲህ ፡ ከእነርሱ ፡
፵፫ ፡ አብልጦ ፡ የሚወደው ፡ ማንኛው ፡ ነው ? ስም
ዖንም ፡ መልሶ ፡— ብዙ ፡ የተወለት ፡ ይመስለ
ኛል ፡ አለ ። እርሱም ፡— በእውነት ፡ ፈረድህ ፡
፵፬ ፡ አለው ። ወደ ፡ ሴቲቱም ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ስም
ዖንን ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— ይህችን ፡ ሴት ፡ ታያ
ለህን ? እኔ ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ ገባሁ ፥ ውኃ ፡
ስንኳ ፡ ለእግሬ ፡ አላቀረብህልኝም ፤ እርስዋ ፡
ግን ፡ በእንባዋ ፡ እግሬን ፡ አራሰች ፡ በጠጕ
፵፭ ፡ ርዋም ፡ አበሰች ። አንተ ፡ አልሳምኸኝም ፤
እርስዋ ፡ ግን ፡ ከገባሁ ፡ ጀምራ ፡ እግሬን ፡ ከመ
፵፮ ፡ ሳም ፡ አላቋረጠችም ። አንተ ፡ ራሴን ፡ ዘይት ፡
አልቀባኸኝም ፤ እርስዋ ፡ ግን ፡ እግሬን ፡ ሽቱ ፡
፵፯ ፡ ቀባች ። ስለዚህ ፡ እልሃለሁ ፥ እጅግ ፡ ወዳለ
ችና ፡ ብዙ ፡ ያለው ፡ ኃጢአትዋ ፡ ተሰርዮላታል ፤
ጥቂት ፡ ግን ፡ የሚሰረይለት ፡ ጥቂት ፡ ይወ
፵፰ ፡ ዳል ። እርስዋንም ፡— ኃጢአትሽ ፡ ተሰርዮል
፵፱ ፡ ሻል ፡ አላት ። ከእርሱም ፡ ጋር ፡ በማዕድ ፡ ተቀ
ምጠው ፡ የነበሩት ፡ በልባቸው ፡— ኃጢአትን ፡
እንኳ ፡ የሚያስተሰርይ ፡ ይህ ፡ ማን ፡ ነው ?
፶ ፡ ይሉ ፡ ጀመር ። ሴቲቱንም ፡— እምነትሽ ፡ አድ
ኖሻል ፤ በሰላም ፡ ሂጂ ፡ አላት ።

ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ እየሰበከና ፡ ስለ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ መንግሥት ፡ የምሥራች ፡ እየተናገረ ፡ በየ
ከተማይቱ ፡ በየመንደሩም ፡ ያልፍ ፡ ነበር ፤
፪ ፡ አሥራ ፡ ሁለቱም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበሩ ፥ ከክ
ፉዎች ፡ መናፍስትና ፡ ከደዌም ፡ ተፈውሰው ፡
የነበሩ ፡ አንዳንድ ፡ ሴቶች ፤ እነርሱም ፡ ሰባት ፡
አጋንንት ፡ የወጡላት ፡ መግደላዊት ፡ የምትባል ፡
፫ ፡ ማርያም ፥ የሄሮድስ ፡ አዛዥ ፡ የኩዛ ፡ ሚስት ፡
ዮሐናም ፡ ሶስናም ፡ ብዙዎች ፡ ሌሎችም ፡ ሆነው ፡
በገንዘባቸው ፡ ያገለግሉት ፡ ነበር ።

፬ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብም ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡ ከከተማዎ
ችም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ በም
፭ ፡ ሳሌ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ተናገራቸው ፡— ዘሪ ፡ ዘሩን ፡
ሊዘራ ፡ ወጣ ። ሲዘራም ፡ አንዳንዱ ፡ በመንገድ ፡
ዳር ፡ ወደቀ ፡ ተረገጠም ፥ የሰማይ ፡ ወፎችም ፡
፮ ፡ በሉት ። ሌላውም ፡ በዓለት ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፥ በበ
ቀለም ፡ ጊዜ ፡ እርጥበት ፡ ስላልነበረው ፡ ደረቀ ።
፯ ፡ ሌላውም ፡ በእሾህ ፡ መካከል ፡ ወደቀ ፥ እሾ
፰ ፡ ሁም ፡ አብሮ ፡ በቀለና ፡ አነቀው ። ሌላውም ፡
በመልካም ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፤ በበቀለም ፡
ጊዜ ፡ መቶ ፡ እጥፍ ፡ አፈራ ። ይህን ፡ በተናገረ ፡
ጊዜ ፡— የሚሰማ ፡ ጆሮ ፡ ያለው ፡ ይስማ ፡ ብሎ ፡
ጮኸ ።

፱ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡— ይህ ፡ ምሳሌ ፡ ምን
፲ ፡ ድር ፡ ነው ? ብለው ፡ ጠየቁት ። እርሱም ፡ እን
ዲህ ፡ አለ ፡— ለእናንተ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መን
ግሥት ፡ ምሥጢር ፡ ማወቅ ፡ ተሰጥቶአችኋል ፤
ስሌሎች ፡ ግን ፡ እያዩ ፡ እንዳያዩ ፡ እየሰሙም ፡
፲፩ ፡ እንዳያስተውሉ ፡ በምሳሌ ፡ ነው ። ምሳሌው ፡
ይህ ፡ ነው ። ዘሩ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ነው ።
፲፪ ፡ በመንገድ ፡ ዳርም ፡ ያሉት ፡ የሚሰሙ ፡ ናቸው ፤
ከዚህ ፡ በኋላም ፡ ዲያብሎስ ፡ ይመጣል ፡ አምነ
ውም ፡ እንዳይድኑ ፡ ቃሉን ፡ ከልባቸው ፡ ይወ
፲፫ ፡ ስዳል ። በዓለት ፡ ላይም ፡ ያሉት ፡ ሲሰሙ ፡
ቃሉን ፡ በደስታ ፡ የሚቀበሉ ፡ ናቸው ፤ እነር
ሱም ፡ ለጊዜው ፡ብቻ ፡ ያምናሉ ፡ እንጂ ፡ በፈ
ተና ፡ ጊዜ ፡ የሚክዱ ፡ሥር ፡ የሌላቸው ፡ ናቸው ።
፲፬ ፡ በእሾህ ፡ መካከልም ፡ የወደቀ ፡ እነዚህ ፡ የሚሰ
ሙት ፡ ናቸው ፤ መንገዳቸውንም ፡ ሄደው ፡ በሕ
ይወት ፡ ዘመን ፡ በአሳብና ፡ በባለ ፡ ጠግነት ፡ ምቾት ፡
፲፭ ፡ ይታነቃሉ ፥ ሙሉ ፡ ፍሬም ፡ አያፈሩም ። በመ
ልካም ፡ መሬት ፡ ላይም ፡ የወደቀ ፡ እነርሱ ፡ በመ
ልካምና ፡ በበጎ ፡ ልብ ፡ ቃሉን ፡ ሰምተው ፡ የሚጠ
ብቁት ፡ በመጽናትም ፡ ፍሬ ፡ የሚያፈሩ ፡ ናቸው ።
፲፮ ፡ መብራትንም ፡ አብርቶ ፡ በዕቃ ፡ የሚከድ
ነው ፡ ወይም ፡ ከአልጋ ፡ በታች ፡ የሚያኖረው ፡
የለም ፥ የሚገቡት ፡ ሰዎች ፡ብርሃኑን ፡ እንዲያዩ ፡
፲፯ ፡ በመቅረዝ ፡ ላይ ፡ያኖረዋል ፡ እንጂ ። የማይገ

፯። ፴፫—፴፭፤ ማቴ. ፲፩፥፲፰—፲፱፤ ማር. ፲፬፥፫—፱፤ ዮሐ. ፲፪፥፩—፰። ፴፱፤ ዘዳግ. ፲፰፥፲፭። ፵፤ ም. ፮፥፲፰። ፶፤ ም. ፰፥፵፰፤ ፲፰፥፵፪፤ ፲፯፥፲፱፤ ፲፰፥፵፪፤ ማቴ. ፱፥፪፤ ማር. ፲፥፶፪።

፰። ፩፡፫፤ ማቴ. ፳፯፥፶፭፤ ፶፮፤ ማር. ፲፭፥፵፥፵፩። ፬—፲፤ ማቴ. ፲፫፥፩—፲፭፤ ማር. ፬፥፩—፲፪። ፲፤ ኢሳ. ፮፥፱። ፲፩—፲፭፤ ማቴ. ፲፫፥፲፰—፳፫፤ ማር. ፬፥፲፫—፳። ፲፮—፲፰፤ ማር. ፬፥፳፩—፳፭፤ ማቴ. ፭፥፲፭። ፲፯፤ ም. ፲፪፥፪፤ ማቴ. ፲፥፳፮።

ስዋ ፡ የተሰወረ ፡ የሰምና ፥ የማይታወቅም ፡ ወደ ፡
፲፰ ግልጥም ፡ የማይመጣ ፡ የተሸሸገ ፡ የለም ። እንግ
ዲህ ፡ እንዴት ፡ እንድትሰሙ ፡ ተጠበቁ ፤ ላለው ፡
ሁሉ ፡ ይሰጠዋልና ፤ ከሌለውም ፡ ሁሉ ፥ ያው ፡
ያለው ፡ የሚመስለው ፡ እንኳ ፡ ይወሰድበታል ።

፲፱ እናቱና ፡ ወንድሞቹም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጡ ፥
ከሕዝቡም ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ሊያገኙት ፡ አልተ
፳ ቻላቸውም ። እናትህና ፡ ወንድሞችህ ፡ ሊያዩህ ፡
ወድደው ፡ በውጭ ፡ ቆመዋል ፡ ብለው ፡ ነገሩት ።
፳፩ እርሱም ፡ መልሶ ፡— እናቴና ፡ ወንድሞቼስ ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ሰምተው ፡ የሚያደርጉት ፡
እነዚህ ፡ ናቸው ፡ አላቸው ።

፳፪ ከዕለታቱም ፡ በአንዱ ፡ እርሱ ፡ ከደቀ ፡ መዛ
ሙርቱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ታንኳ ፡ ገብቶ ፡— ወደ ፡
ባሕር ፡ ማዶ ፡ እንሻገር ፡ አላቸው ፤ ተነሡም ።
፳፫ ሲሄዱም ፡ አንቀላፋ ። ዓውሎ ፡ ነፋስም ፡ በባ
ሕር ፡ ላይ ፡ ወረደ ፥ ውኃም ፡ ታንኳይቱን ፡ ይሞላ ፡
፳፬ ነበርና ፡ ይጨነቁ ፡ ነበር ። ቀርበውም ፡— አቤቱ ፥
አቤቱ ፡ ጠፋን ፡ እያሉ ፡ አስነሡት ። እርሱም ፡
ነቅቶ ፡ ነፋሱንና ፡ የውኃውን ፡ ማዕበል ፡ ገሠጻ
፳፭ ቸው ፤ ተዉም ፥ ጸጥታም ፡ ሆነ ። እርሱም ፡—
እምነታችሁ ፡ የት ፡ ነው ? አላቸው ። ፈርተ
ውም ፡ ተደነቁ ፥ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡— እን
ዲህ ፡ ነፋሳትንና ፡ ውኃን ፡ እንኳ ፡ የሚያዝ ፡ ለእ
ርሱም ፡ የሚታዘዙለት ፡ ይህ ፡ ማን ፡ ነው ?
አሉ ።

፳፮ በገሊላም ፡ አንጻር ፡ ወዳለችው ፡ ወደ ፡ ጌር
፳፯ ጌሴኖን ፡ አገር ፡ በታንኳ ፡ ደረሱ ። ወደ ፡ ምድ
ርም ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ አጋንንት ፡ ያደሩበት ፡ አንድ ፡
ሰው ፡ ከከተማ ፡ ወጥቶ ፡ ተገናኘው ፥ ከብዙ ፡
ዘመንም ፡ ጀምሮ ፡ ልብስ ፡ ሳይለብስ ፡ በመቃ
፳፰ ብር ፡ እንጂ ፡ በቤት ፡ አይኖርም ፡ ነበር ። ኢየ
ሱስንም ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ጮኸ ፡ በፊቱ ፡ ተደፋ ፡ በታ
ላቅ ፡ ድምፅም ፡— የልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡
ልጅ ፡ ኢየሱስ ፡ ሆይ ፥ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አለኝ ?
፳፱ እንዳትሣቀየኝ ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለ ። ርኩሱን ፡
መንፈስ ፡ ከሰውዬው ፡ እንዲወጣ ፡ ያዘው ፡ ነበ
ርና ። ብዙ ፡ ዘመንም ፡ ይዞት ፡ ነበርና ፥ በሰንሰ
ለትና ፡ በእግር ፡ ብረትም ፡ ታስሮ ፡ ይጠበቅ ፡
ነበር ፤ እስራቱንም ፡ ሰብሮ ፡ በጋኔኑ ፡ ወደ ፡
፴ ምድረ ፡ በዳ ፡ ይነዳ ፡ ነበር ። ኢየሱስም ፡—
ስምህ ፡ ማን ፡ ነው ? ብሎ ፡ ጠየቀው ። እርሱም ፡
ብዙዎች ፡ አጋንንት ፡ ገብተውበት ፡ ነበርና ፡—
፴፩ ሌጌዎን ፡ አለው ። ወደ ፡ ጥልቁም ፡ ሊሄዱ ፡ እን
፴፪ ዳያዛቸው ፡ ለመኑት ። በዚያም ፡ በተራራው ፡
የብዙ ፡ እሪያ ፡ መንጋ ፡ ይሰማራ ፡ ነበር ፤ ወደ ፡
እነርሱም ፡ ሊገቡ ፡ እንዲፈቅድላቸው ፡ ለመኑት ፤
፴፫ ፈተደላቸውም ። አጋንንትም ፡ ከሰውዬው ፡
ወጥተው ፡ ወደ ፡ እሪያዎች ፡ ገቡ ፥ መንጋውም ፡
ከአፋፉ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ተጣደፉና ፡ ሰጠሙ ።
፴፬ እረኞችም ፡ የሆነውን ፡ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ሸሽተው ፡
፴፭ በከተማውና ፡ በአገሩ ፡ አወሩት ። የሆነውን ፡
ነገር ፡ ሊያዩ ፡ ወጥተውም ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡
መጡ ፥ አጋንንትም ፡ የወጡለትን ፡ ሰው ፡ ለብሶ ፡
ልቡም ፡ ተመልሶ ፡ በኢየሱስ ፡ እግር ፡ አጠገብ ፡
፴፮ ተቀምጦ ፡ አገኙትና ፡ ፈሩ ። ያዩትም ፡ ደግሞ ፡
አጋንንት ፡ ያደሩበት ፡ ሰው ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡
፴፯ ዳነ ፡ አወሩላቸው ። በዙሪያውም ፡ በጌርጌሴኖን ፡
አገር ፡ ያሉት ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ታላቅ ፡ ፍርሃት ፡
ይዞአቸዋልና ፡ ከእነርሱ ፡ እንዲሄድ ፡ ለመኑት ፤
፴፰ ዘታንኳም ፡ ገብቶ ፡ ተመለሰ ። አጋንንት ፡ የወ
ጡለት ፡ ሰውም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡
፴፱ ለመነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡— ወደ ፡ ቤትህ ፡ ተመ
ለስ ፥ እግዚአብሔር ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡
እንዳደረግልህ ፡ ንገር ፡ ብሎ ፡ አሰናበተው ።
ኢየሱስም ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡ እንዳ
ደረገለት ፡ በከተማው ፡ ሁሉ ፡ እየሰበከ ፡ ሄደ ።

፵ ኢየሱስም ፡ በተመለሰ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ ይጠብ
፵፩ ቁት ፡ ነበርና ፡ ሕዝቡ ፡ ተቀበሉት ። እነሆም ፥
ኢያኢሮስ ፡ የሚባል ፡ ሰው ፡ መጣ ፥ እርሱም ፡
የምኩራብ ፡ አለቃ ፡ ነበረ ፤ በኢየሱስም ፡ እግር ፡
ላይ ፡ ወድቀ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ እንዲገባ ፡ ለመነው ፤
፵፪ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ የሆናት ፡ አንዲት ፡ ቤት ፡
ልጅ ፡ ነበረችውና ፤ እርሰዋም ፡ ለሞት ፡ ቀርባ ፡
ነበረች ።

ሲሄድም ፡ ሕዝቡ ፡ ያጨናንቁት ፡ ነበር ።
፵፫ ከአሥራ ፡ ሁለት ፡ ዓመትም ፡ ጀምሮ ፡ ደም ፡ የሚ
ፈሳት ፡ ቤት ፡ ነበረች ፥ ትዳርዋንም ፡ ሁሉ ፡ ለባለ ፡
መድኃኒቶች ፡ ከሰራ ፡ ማንም ፡ ሊፈውሳት ፡ አል
፵፬ ተቻለውም ። በኋላውም ፡ ቀርባ ፡ የልብሱን ፡
ጫፍ ፡ ዳሰሰች ፥ የደምዋም ፡ ፈሳሽ ፡ በዚያን ፡
፵፭ ጊዜ ፡ ቆመ ። ኢየሱስም ፡— የዳሰሰኝ ፡ ማን ፡
ነው ? አለ ። ሁሉም ፡ በካዱ ፡ ጊዜ ፥ ጴጥሮስና ፡
ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡— አቤቱ ፥ ሕዝቡ ፡ ያጨ
ናንቁሃልና ፡ ያጋፉሃማል ፤ የዳሰሰኝ ፡ ማን ፡ ነው ፡
፵፮ ትላለህን ? አሉ ። ኢየሱስ ፡ ግን ፡— አንድ ፡
ሰው ፡ ዳሰሰኛል ፥ ኃይል ፡ ከእኔ ፡ እንደ ፡ ወጣ ፡
፵፯ እኔ ፡ አውቃለሁና ፡ አለ ። ሴቲቱም ፡ እንዳል
ተሰወረች ፡ በየች ፡ ጊዜ ፡ እየተንቀጠቀጠች ፡
መጥታ ፡ በፊቱ ፡ ተደፋች ፥ በምን ፡ ምክንያትም ፡
እንደ ፡ ዳሰሰችው ፡ ፈጥናም ፡ እንደ ፡ ተፈወሰች ፡
፵፰ በሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ አወራች ። እርሱም ፡—
ልጄ ፡ ሆይ ፥ እምነትሽ ፡ አድኖሻል ፤ በሰላም ፡
ሂጂ ፡ አላት ።

፵፱ እርሱም ፡ ገና ፡ ሲናገር ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ከም
ኩራብ ፡ አለቃው ፡ ቤት ፡ መጥቶ ፡— ልጅህ ፡
ሞታለች ፤ እንግዲህ ፡ መምህሩን ፡ አታድክም ፡
፶ አለ ። ኢየሱስ ፡ ግን ፡ ሰምቶ ፡— አትፍራ ፤
እመን ፡ ብቻ ፡ ትድንማለች ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።
፶፩ ወደ ፡ ቤትም ፡ ሲገባ ፡ ከጴጥሮስና ፡ ከያዕቆብ ፡
ከዮሐንስም ፡ ከብላቴናይቱም ፡ አባትና ፡ እናት ፡
በቀር ፡ ማንም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይገባ ፡ ዘንድ ፡

፰ ። ፲፯ ፤ ም. ፲፱ ፡ ፳፮ ፤ ማቴ. ፲፫ ፡ ፲፪ ፤ ማር. ፬ ፡ ፳፭ ። ፲፱—፳፩ ፤ ማቴ. ፲፪ ፡ ፵፮—፶ ፤ ማር. ፫ ፡ ፴፩—፴፭ ። ፳፪—፳፭ ፤ ማቴ. ፰ ፡ ፳፫—፳፯ ፤ ማር. ፬ ፡ ፴፭—፵፩ ። ፳፮—፴፱ ፤ ማቴ. ፰ ፡ ፳፰—፴፬ ፤ ማር. ፭ ፡ ፩—፳ ። ፴፩ ፤ ራእ. ፱ ፡ ፩ ። ፵፩—፶፮ ፤ ማቴ. ፱ ፡ ፲፰—፳፮ ፤ ማር. ፭ ፡ ፳፪—፵፫ ። ፵፬ ፤ ም. ፮ ፡ ፲፱ ። ፵፰ ፤ ም. ፯ ፡ ፶ ። ፶፩ ፤ ም. ፱ ፡ ፳፰ ።

፶፫ አልፈቀደም ። ሁሉም ፡ እያለቀሱላት ፡ ዋይ ፡ ዋይ ፡ ይሉ ፡ ነበር ። እርሱ ፡ ግን ፡— አታል ቅሱ ፤ ተኝታለች ፡ እንጂ ፡ አልሞተችም ፡ አለ ።
፶፫ እንደ ፡ ሞተችም ፡ አውቀው ፡ በጣም ፡ ሳቁበት ።
፶፬ እርሱ ፡ ግን ፡ እጅዋን ፡ ይዞ ፡— አንቺ ፡ ብላቴና ፥
፶፭ ተነሺ ፡ ብሎ ፡ ጮኸ ። ነፍስዋም ፡ ተመለሰች ፥ ፈጥናም ፡ ቆመች ፥ የምትበላውንም ፡ እንዲሰጡ
፶፮ አት ፡ አዘዘ ። ወላጆችዋም ፡ ተገረሙ ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ የሆነውን ፡ ለማንም ፡ እንዳይነግሩ ፡ አዘ ዛቸው ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ እሥራ ፡ ሁለቱንም ፡ ሐዋርያት ፡ በአንድነት ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ጠርቶ ፡ በአጋንንት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ደዌንም ፡ ይፈውሱ ፡ ዘንድ ፡ ኃይልና ፡ ሥልጣን ፡
፪ ሰጣቸው ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ መንግሥት ፡ እንዲሰብኩና ፡ ድውዮችን ፡ እንዲፈውሱ ፡ ላካ
፫ ቸው ፥ እንዲህም ፡ አላቸው ፡— በትርም ፡ ቢሆን ፥ ከረጢትም ፡ ቢሆን ፥ እንጀራም ፡ ቢሆን ፥ ብርም ፡ ቢሆን ፡ ለመንገድ ፡ ምንም ፡ አትያዙ ፥ ሁለት ፡
፬ እጀ ፡ ጠባብም ፡ አይሁንላችሁ ። በማናቸውም ፡ በምትገቡበት ፡ ቤት ፡ በዚያ ፡ ተቀመጡ ከዚ
፭ ያም ፡ ውጡ ። ማናቸውም ፡ የማይቀበሉአችሁ ፡ ቢሆኑ ፥ ከዚያ ፡ ከተማ ፡ ወጥታችሁ ፡ ምስክር ፡ እንዲሆንባቸው ፡ ከእግራችሁ ፡ ትቢያ ፡ አራ
፮ ግፉ ። ወጥተውም ፡ ወንጌልን ፡ እየሰበኩና ፡ በስፍራው ፡ ሁሉ ፡ እየፈወሱ ፡ በየመንደሩ ፡ ያልፉ ፡ ነበር ።
፯ የአራተኛው ፡ ክፍል ፡ ገዥ ፡ ሄሮድስም ፡ የተ ደረገውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ሰምቶ ፥ አንዳንድ ፡
፰ ሰዎች ፡— ዮሐንስ ፡ ከሙታን ፡ ተነሣ ፥ ሌሎ ችም ፡— ኤልያስ ፡ ተገለጠ ፥ ሌሎችም ፡— ከቀ ደሙት ፡ ነቢያት ፡ አንዱ ፡ ተነሥቶአል ፡ ይሉ ፡
፱ ስለ ፡ ነበሩ ፡ አመነታ ። ሄሮድስም ፡— ዮሐንስ ንስ ፡ እኔ ፡ ራሱን ፡ አስቈረጥሁት ፤ ይህ ፡ እን ዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ የምሰማበት ፡ ማን ፡ ነው ? አለ ። ሊያየውም ፡ ይሻ ፡ ነበር ።
፲ ሐዋርያትም ፡ ተመልሰው ፡ ያደረጉትን ፡ ሁሉ ፡ ነገሩት ። ከእርሱ ፡ ጋርም ፡ ወስዶአቸው ፡ ቤተ ፡ ሳይዳ ፡ ከምትባል ፡ ከተማ ፡ አጠገብ ፡ ወደ ፡
፲፩ ምድረ ፡ በዳ ፡ ለብቻው ፡ ፈቀቅ ፡ አለ ። ሕዝ ቡም ፡ አውቀው ፡ ተከተሉት ፤ ተቀብሎአቸ ውም ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ይነግራ ቸው ፡ ነበር ፥ መፈወስ ፡ ያስፈለጋቸውንም ፡ ፈወ
፲፪ ሳቸው ። ቀኑም ፡ ይመሽ ፡ ጀመር ፤ እሥራ ፡ ሁለቱም ፡ ቀርበው ፡— በዚህ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ነንና ፡ በዙሪያ ችን ፡ ወዳሉ ፡ መንደሮችና ፡ ገጠ ሮች ፡ ሄደው ፡ እንዲያድሩና ፡ ምግብ ፡ እንዲያገኙ ፡
፲፫ ሕዝቡን ፡ አሰናብት ፡ አሉት ። እርሱ ፡ ግን ፡— እናንተ ፡ የሚበሉትን ፡ ስጡአቸው ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡— ሄደን ፡ ለዚህ ፡ ሁሉ ፡ ሕዝብ ፡ ምግብ ፡ ካልገዛን ፥ ከአምስት ፡ እንጀራና ፡ ከሁ
፲፬ ለት ፡ ዓሣ ፡ የሚበልጥ ፡ የለንም ፡ አሉት ፤ አም ስት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ያህሉ ፡ ነበርና ። ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡— በየክፍሉ ፡ አምሳ ፡ አምሳውን ፡
፲፭ አስቀምጡአቸው ፡ አላቸው ። እንዲህም ፡ አደ
፲፮ ረጉ ፡ ሁሉንም ፡ አስቀመጡአቸው ። አምስቱ ንም ፡ እንጀራና ፡ ሁለቱን ፡ ዓሣ ፡ ይዞ ፥ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አሻቅቦ ፡ አየና ፡ ባረካቸው ፡ ቈርሶም ፡ ለሕዝቡ ፡ እንዲያቀርቡ ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡
፲፯ ሰጠ ። ሁሉም ፡ በልተው ፡ ጠገቡ ፥ ከእነርሱም ፡ የተረፈውን ፡ ቍርስራሽ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ መሶብ ፡ ወሰዱ ።
፲፰ ለብቻውም ፡ ሲጸልይ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ከእ ርሱ ፡ ጋር ፡ ነበሩና ፡— ሕዝቡ ፡ እኔ ፡ ማን ፡ እንደ ፡
፲፱ ሆንሁ ፡ ይላሉ ? ብሎ ፡ ጠየቃቸው ። እነር ሱም ፡ መለሰው ፡— መጥምቁ ፡ ዮሐንስ ፥ ሌሎ ችም ፡— ኤልያስ ፥ ሌሎችም ፡— ከቀደሙት ፡ ነቢያት ፡ አንዱ ፡ ተነሥቶአል ፡ ይላሉ ፡ አሉት ።
፳ እናንተስ ፡ እኔ ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ትላላችሁ ? አላቸው ። ጴጥሮስም ፡ መልሶ ፡— የእግዚአብ
፳፩፡፳፪ ሔር ፡ የተቀባህ ፡ ነህ ፡ አለ ። እርሱ ፡ ግን ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ ብዙ ፡ መከራ ፡ ሊቀበል ፡ በሽማግሌዎ ችም ፡ በካህናት ፡ አለቆችም ፡ በጻፎችም ፡ ሊጣል ፡ ሊገደልም ፡ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ሊነሣ ፡ ይገ ባዋል ፡ ብሎ ፡ ለማንም ፡ ይህን ፡ እንዳይናገሩ ፡ አስጠንቅቆ ፡ አዘዘ ።
፳፫ ለሁሉም ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— በኋላዬ ፡ ሊመጣ ፡ የሚወድ ፡ ቢኖር ፥ ራሱን ፡ ይካድ ፡ መስ ቀሉንም ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ተሸክሞ ፡ ይከተለኝ ።
፳፬ ነፍሱን ፡ ሊያድን ፡ የሚወድ ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋታ ልና ፤ ስለ ፡ እኔ ፡ ነፍሱን ፡ የሚያጠፋ ፡ ሁሉ ፡
፳፭ ግን ፡ እርሱ ፡ ያድናታል ። ሰው ፡ ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ አትርፎ ፡ ራሱን ፡ ቢያጠፋ ፡ ወይም ፡ ቢያጐድል ፡
፳፮ ምን ፡ ይጠቀመዋል ? በእኔና ፡ በቃሌ ፡ የሚያ ፍር ፡ ሁሉ ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ በክብሩ ፡ በአባቱና ፡ በቅዱሳን ፡ መላእክቱ ፡ ክብርም ፡ ሲመጣ ፡ በእ
፳፯ ርሱ ፡ ያፍርበታል ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ በዚህ ፡ ከሚቆሙት ፡ ሰዎች ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ እስኪያዩ ፡ ድረስ ፡ ሞትን ፡ የማይ ቀምሱ ፡ አንዳንድ ፡ አሉ ።
፳፰ ከዚህም ፡ ቃል ፡ በኋላ ፡ስምንት ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ ጴጥሮስንና ፡ ዮሐንስን ፡ ያዕቆብንም ፡
፳፱ ይዞ ፡ ሊጸልይ ፡ ወደ ፡ ተራራ ፡ ወጣ ። ሲጸል

፰። ፶፭ ፤ ማቴ. ፰ ፥ ፱ ።

፱። ፩—፭ ፤ ማቴ. ፲ ፥ ፩ ፡ ፭ ፡ ፯—፲፬ ፤ ማር. ፮ ፥ ፯—፲፩ ። ፭ ፤ ሥራ. ፲ ፥ ፲፩ ። ፯—፱ ፤ ማቴ. ፲፬ ፥ ፩ ፲፬ ፤ ማር. ፮ ፥ ፲፬—፳፱ ። ፲—፲፯ ፤ ማቴ. ፲፬ ፥ ፲፫—፳፩ ፤ ማር. ፮ ፥ ፴—፵፬ ፤ ዮሐ. ፮ ፥ ፩—፲፫ ። ፲፫—፲፯ ፤ ፪ ነገሥ. ፬ ፥ ፵፪—፵፬ ። ፲፰—፳ ፤ ዮሐ. ፮ ፥ ፷፰ ፤ ማቴ. ፲፮ ፥ ፲፫—፲፮ ፤ ማር. ፰ ፥ ፳፯—፳፱ ። ፳ ፤ ዮሐ. ፮ ፥ ፷፱ ። ፳፩ ፤ ማቴ. ፲፮ ፥ ፳ ፤ ማር. ፰ ፥ ፴ ። ፳፪—፳፯ ፤ ማቴ. ፲፮ ፥ ፳፩—፳፰ ፤ ማር. ፰ ፥ ፴፩—፱ ፥ ፩ ። ፳፪ ፤ ሉቃ. ፳፬ ፤ ዮሐ. ፲፱ ፥ ፳፯ ፡ ፳፰ ፤ ማቴ. ፲፯ ፥ ፳፪ ፤ ዮሐ. ፲፪ ፥ ፳፭ ፡ ፳፮ ። ፳፫ ፡ ፳፬ ፤ ዮሐ. ፲፫ ፥ ፳፫ ፤ ዮሐ. ፲፪ ፥ ፳፭ ። ፳፮ ፤ ማቴ. ፲ ፥ ፴፫ ። ፳፰—፴፮ ፤ ማቴ. ፲፯ ፥ ፩—፰ ፤ ማር. ፱ ፥ ፪—፰ ። ፳፰ ፤ ዮሐ. ፭ ፥ ፲፯ ፤ ፭ ፥ ፲፮ ።

ይም ፡ የፊቱ ፡ መልክ ፡ ተለወጠ ፤ ልብሱም ፡ ተብ ፴ ለጭልጭሎ ፡ ነጭ ፡ ሆነ ። እነሆም ÷ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ እነርሱም ፡ ሙሴና ፡ ኤልያስ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይነ ፴፩ ጋገሩ ፡ ነበር ፤ በክብርም ፡ ታይተው ፡ በኢየሩሳ ሌም ፡ ሊፈጽም ፡ ስላለው ፡ ስለ ፡ መውጣቱ ፡ ይና ፴፪ ገሩ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ ጴጥሮስና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ እንቅልፍ ፡ ከበደባቸው ፤ ነቅተው ፡ ግን ፡ ክብሩንና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ቆመው ፡ የነበሩ ፴፫ ትን ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ አዩ ። ከእርሱም ፡ ሲለዩ ፡ ጴጥሮስ ፡ ኢየሱስን ፡— አቤቱ ÷ በዚህ ፡ መሆን ፡ ለእኛ ፡ መልካም ፡ ነውና ፡ አንድ ፡ ለአንተ ፡ አን ድም ፡ ለሙሴ ፡ አንድም ፡ ለኤልያስ ፡ ሦስት ፡ ዳስች ፡ እንሥራ ፡ አለው ፤ የሚለውንም ፡ አያ ፴፬ ውቅም ፡ ነበር ። ይህንም ፡ ሲናገር ፡ ደመና ፡ መጣና ፡ ጋረዳቸው ፤ ወደ ፡ ደመናውም ፡ ሲገቡ ፡ ፴፭ ሳሉ ፡ ፈሩ ። ከደመናውም ፡— የመረጥሁት ፡ ልጄ ፡ ይህ ፡ ነው ÷ እርሱን ፡ ስሙት ፡ የሚል ፡ ፴፮ ድምፅ ፡ መጣ ። ድምፁም ፡ ከመጣ ፡ በኋላ ፡ ኢየ ሱስ ፡ ብቻውን ፡ ሆኖ ፡ ተገኘ ። እነርሱም ፡ ዝም ፡ አሉ ፡ ካዩትም ፡ ነገር ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ ምንም ፡ ለማንም ፡ አላወሩም ።

፴፯ በነገውም ፡ ከተራራ ፡ ሲወርዱ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ፴፰ ተገናኙት ። እነሆም ÷ ከሕዝቡ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ እያለ ፡ ጮኸ ፡— መምህር ፡ ሆይ ÷ ለእኔ ፡ አንድ ፡ ልጅ ፡ ነውና ፡ ልጄን ፡ እንድታይልኝ ፡ ፴፱ እለምንሃለሁ ። እነሆም ÷ ጋኔን ፡ ይይዘዋል ÷ ድንገትም ፡ ይጮኻል ፡ አረፋም ፡ እያስደፈቀው ፡ ያንፈራግጠዋል ÷ እየቀጠቀጠም ፡ በጭንቅ ፡ ፵ ይለቀዋል ፤ ደቀ ፡ መዛሙርትህንም ፡ እንዲያወ ፵፩ ጡት ፡ ለመንሁ ÷ አልቻሉምም ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡— እናንተ ፡ የማታምን ፡ ጠማማ ፡ ትውልድ ÷ እስከ ፡ መቼ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እኖራለሁ ? እስከ ፡ መቼስ ፡ እታገሣችኋለሁ ? ልጅህን ፡ ወደ ፵፪ ዚህ ፡ አምጣው ፡ አለ ። ሲቀርብም ፡ ጋኔኑ ፡ ጣለ ውና ፡ አንፈራገጠው ፤ ኢየሱስ ፡ ግን ፡ ርኵሱን ፡ መንፈስ ፡ ገሥጾ ፡ ብላቴናውን ፡ ፈወሰው ፡ ለአ ፵፫ ባቱም ፡ መለሰው ። ሁሉም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ታላቅነት ፡ የተነሣ ፡ ተገረሙ ።

ሁሉም ፡ ኢየሱስ ፡ ባደረገው ፡ ሁሉ ፡ ሲደነቁ ÷ ፵፬ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡— የሰው ፡ ልጅ ፡ በሰው ፡ እጅ ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ አለውና ፡ እናንተ ፡ ይህን ፡ ፵፭ ቃል ፡ በጆሮአችሁ ፡ አኑሩ ፡ አለ ። እነርሱ ፡ ግን ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ አላስተዋሉም ÷ እንዳይገባ ቸውም ፡ ተሰውሮባቸው ፡ ነበር ፤ ስለዚህ ፡ ነገ ርም ፡ እንዳይጠይቁት ፡ ፈሩ ።

፵፮ ከእነርሱም ፡ ማን ፡ እንዲበልጥ ፡ ክርክር ፡ ተነ ፵፯ ሣባቸው ። ኢየሱስም ፡ የልባቸውን ፡ አሳብ ፡ አውቆ ፡ሕፃንን ፡ ያዘ ፤ በአጠገቡም ፡ አቁሞ ፡— ፵፰ ማንም ፡ ይህን ፡ ሕፃን ፡ በስሜ ፡ የሚቀበል ፡ እኔን ፡ ይቀበላል ፤ የሚቀበለኝም ፡ ሁሉ ፡ የላከኝን ፡ ይቀ በላል ፤ ከሁላችሁ ፡ የሚያንስ ፡ እርሱ ፡ ታላቅ ፡ ነውና ፡ አላቸው ።

፵፱ ዮሐንስም ፡ መልሶ ፡— አቤቱ ÷ አንድ ፡ ሰው ፡ በስምህ ፡ አጋንንትን ፡ ሲያወጣ ፡ አየነው ÷ ከእኛ ፡ ጋርም ፡ ስለማይከተል ፡ ከለከልነው ፡ አለው ። ፶ ኢየሱስ ፡ ግን ፡— የማይቃወማችሁ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ነውና ፡ አትከልክሉት ፡ አለው ።

፶፩ የሚወጣበትም ፡ ወራት ፡ በቀረበ ፡ጊዜ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ለመሄድ ፡ ፊቱን ፡ አቀና ÷ በፊ ፶፪ ቱም ፡ መልክተኞችን ፡ ላደደ ። ሄደውም ፡ ሊያ ሰናዱለት ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ ወደ ፡ ሳምራውያን ፡ መንደር ፡ ገቡ ፤ ፊቱም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ፶፫ እንደሚሄድ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ አልተቀበሉትም ። ፶፬ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ያዕቆብና ፡ ዮሐንስ ፡ አይ ተው ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ ኤልያስ ፡ ደግሞ ፡ እንዳደ ረገ ፡ እሳት ፡ ከሰማይ ፡ ወርዶ ፡ ያጥፋቸው ፡ እንል ፡ ፶፭ ዘንድ ፡ ትወዳለህን ? አሉት ። እርሱ ፡ ግን ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ገሠጻቸውና ፡— ምን ፡ ዓይነት ፡ ፶፮ መንፈስ ፡ እንደ ፡ ሆናችሁ ፡ አታውቁም ፤ የሰው ፡ ልጅ ፡ የሰውን ፡ ነፍስ ፡ ሊያድን ፡ እንጂ ፡ ሊያ ጠፋ ፡ አልመጣም ፡ አለ ። ወደ ፡ ሌላ ፡ መንደ ርም ፡ ሄዱ ።

፶፯ እነርሱም ፡ በመንገድ ፡ ሲሄዱ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ ወደምትሄድበት ፡ ሁሉ ፡ እከተ ፶፰ ልሃለሁ ፡ አለው ። ኢየሱስም ፡— ለቀበሮዎች ፡ ጕድጓድ ፡ ለሰማይም ፡ ወፎች ፡ መሳፈሪያ ፡ አላ ቸው ÷ ለሰው ፡ ልጅ ፡ ግን ፡ ራሱን ፡ የሚያስጠ ፶፱ ጋበት ፡ የለውም ፡ አለው ። ሌላውንም ፡— ተከ ተለኝ ፡ አለው ። እርሱ ፡ ግን ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ አስቀድሜ ፡ ልሂድና ፡ አባቴን ፡ እቀብር ፡ ዘንድ ፡ ፷ ፍቀድልኝ ፡ አለ ። ኢየሱስም ፡— ሙታናቸ ውን ፡ እንዲቀብሩ ፡ ሙታንን ፡ ተዋቸው ፤ አን ተስ ፡ ሄደህ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ ፷፩ ስበክ ፡ አለው ። ደግሞ ፡ ሌላው ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ እከተልሃለሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አስቀድሜ ፡ ከቤቱ ፡ ፷፪ ሰዎች ፡ እንድሰናበት ፡ ፍቀድልኝ ፡ አለ ። ኢየ ሱስ ፡ ግን ፡— ማንም ፡ ዕርፍ ፡ በእጁ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ የሚመለከት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መንግ ሥት ፡ የተገባ ፡ አይደለም ፡ አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ጌታ ፡ ሌሎቹን ፡ ሰብዓ ፡ ሾመ ÷ ሁለት ፡ ሁለትም ፡ አድርጎ ፡ እርሱ ፡ ሊሄድበት ፡ ወዳለው ፡ ከተማና ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ላካ ፪ ቸው ። አላቸውም ፡— መከሩስ ፡ ብዙ ፡ ነው ÷ ሠራተኞች ፡ ግን ፡ ጥቂቶች ፡ ናቸው ፤ እንግዲህ ፡ የመከሩን ፡ ጌታ ፡ ለመከሩ ፡ ሠራተኞች ፡ እንዲ ፫ ልክ ፡ ለምኑት ። ሂዱ ፤ እነሆ ÷ እንደ ፡ በጎች ፡

፱። [illegible]

፲። [illegible]

፫፤ በተኵላዎች ፡ መካከል ፡ እልካችኋለሁ ። ፬፤ ኮረጆም ፡ ከረጢትም ፡ ጫማም ፡ አትያዙ ፤ በመንገድም ፡ ለማንም ፡ እጅ ፡ አትንሡ ። ፭፤ ወደምትገቡበት ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ አስቀድማችሁ ፦ ሰላም ፡ ለዚህ ፡ ቤት ፡ ይሁን ፡ በሉ ። ፮፤ በዚያም ፡ የሰላም ፡ ልጅ ፡ ቢኖር ፥ ሰላማችሁ ፡ ያድርበታል ፤ አለዚያም ፡ ይመለስላችኋል ። ፯፤ በዚያም ፡ ቤት ፡ ከእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ካለው ፡ እየበላችሁና ፡ እየጠጣችሁ ፡ ተቀመጡ ፤ ለሠራተኛ ፡ ደመወዙ ፡ ይገባዋልና ። ከቤት ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ አትተላለፉ ። ፰፤ ወደምትገቡበትም ፡ ከተማ ፡ ሁሉ ፡ ቢቀበሉአችሁ ፥ ፱፤ ያቀረቡላችሁን ፡ ብሉ ፤ በእርስዋም ፡ ያሉትን ፡ ድውዮችን ፡ ፈውሱና ፦ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ቀረበች ፡ በሉአቸው ። ፲፤ ነገር ፡ ግን ፡ ወደምትገቡበት ፡ ከተማ ፡ ሁሉ ፡ ባይቀበሉአችሁ ፥ ወደ ፡ አደባባይዋ ፡ ወጥ ፲፩፤ ታችሁ ፦ ከከተማችሁ ፡ የተጣበቀብንን ፡ ትቢያ ፡ እንኳን ፡ እናራግፍላችኋለን ፤ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ እንደ ፡ ቀረ ፲፪፤ በች ፡ ይህን ፡ እወቁ ፡ በሉ ። እላችኋለሁ ፥ በዚያን ፡ ቀን ፡ ከዚያች ፡ ከተማ ፡ ይልቅ ፡ ለሰዶም ፡ ይቀልላታል ።

፲፫፤ ወዮልሽ ፡ ኮራዚን ፥ ወዮልሽ ፡ ቤተ ፡ ሳይዳ ፤ በእናንተ ፡ የተደረገው ፡ ተአምራት ፡ በጢሮስና ፡ በሲዶና ፡ ተደርጎ ፡ ቢሆን ፥ ማቅ ፡ ለብሰው ፡ በአመድም ፡ ተቀምጠው ፡ ከብዙ ፡ጊዜ ፡ በፊት ፡ ፲፬፤ ንስሐ ፡ በገቡ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በፍርድ ፡ ከእናንተ ፡ ይልቅ ፡ ለጢሮስና ፡ ለሲዶና ፡ ይቀ ፲፭፤ ልላቸዋል ። አንቺም ፡ ቅፍርናሆም ፥ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ከፍ ፡ አልሽን ? ወደ ፡ ሲኦል ፡ ትወርጃ ለሽ ።

፲፮፤ የሚሰማችሁ ፡ እኔን ፡ ይሰማል ፥ እናንተንም ፡ የጣለ ፡ እኔን ፡ ይጥላል ፤ እኔንም ፡ የጣለ ፡ የላከ ኝን ፡ ይጥላል ።

፲፯፤ ሰብዓውም ፡ በደስታ ፡ ተመልሰው ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ አጋንንት ፡ ስንኳ ፡ በስምህ ፡ ተገዝተው ፲፰፤ ልናል ፡ አሉት ። እንዲህም ፡ አላቸው ፦ ሰይ ጣንን ፡ እንደ ፡ መብረቅ ፡ ከሰማይ ፡ ሲወድቅ ፡ ፲፱፤ አየሁ ። እነሆ ፥ እባቡንና ፡ጊንጡን ፡ ትረግጡ ፡ ዘንድ ፥ በጠላትም ፡ ኃይል ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሥል ጣን ፡ ሰጥቻችኋለሁ ፤ የሚጐዳችሁም ፡ ምንም ፡ ፳፤ የለም ። ነገር ፡ ግን ፡ መናፍስት ፡ ስለ ፡ ተገዙላ ችሁ ፡ በዚህ ፡ ደስ ፡ አይበላችሁ ፥ ስማችሁ ፡ ግን ፡ በሰማያት ፡ ስለ ፡ ተጻፈ ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ።

፳፩፤ በዚያን ፡ ሰዓት ፡ ኢየሱስ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሐሤት ፡ አደረገና ፦ የሰማይና ፡ የምድር ፡ ጌታ ፡ አባት ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ ከጥበበኞችና ፡ ከአስተዋ ዮች ፡ ሰውረህ ፡ ለሕፃናት ፡ ስለ ፡ ገለጥህላቸው ፡ አመሰግንሃለሁ ፤ አዎን ፡ አባት ፡ ሆይ ፥ ፈቃድህ ፡ ፳፪፤ በፊትህ ፡ እንዲህ ፡ ሆኖአልና ። ሁሉ ፡ ከአባቴ ፡ ዘንድ ፡ ተሰጥቶኛል ፥ ወልድንም ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከአብ ፡ በቀር ፡ የሚያውቅ ፡ የለም ፥ አብ ንም ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከወልድ ፡ በቀር ፡ ወል ድም ፡ ሊገልጥለት ፡ ከሚፈቅድ ፡ በቀር ፡ የሚ ያውቅ ፡ የለም ፡ አለ ።

፳፫፤ ወደ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ለብቻቸው ፦ የምታዩትን ፡ የሚያዩ ፡ ዓይኖች ፡ ፳፬፤ ብፁዓን ፡ ናቸው ። እላችኋለሁና ፥ እናንተ ፡ የምታዩትን ፡ ብዙዎች ፡ ነቢያትና ፡ ነገሥታት ፡ ሊያዩ ፡ ወደዱ ፡ አላዩምም ፥ የምትሰሙትንም ፡ ሊሰሙ ፡ ወደዱ ፡ አልሰሙም ፡ አለ ።

፳፭፤ እነሆም ፥ አንድ ፡ ሕግ ፡ አዋቂ ፡ ሊፈትነው ፡ ተነሥቶ ፦ መምህር ፡ ሆይ ፥ የዘላለምን ፡ ሕይ ወት ፡ እንድወርስ ፡ ምን ፡ ላድርግ ? አለው ። ፳፮፤ እርሱም ፦ በሕግ ፡ የተጻፈው ፡ ምንድር ፡ ነው ? ፳፯፤ እንዴትስ ፡ ታነባለህ ? አለው ። እርሱም ፡ መልሶ ፦ ጌታ ፡ አምላክህን ፡ በፍጹም ፡ልብህ ፡ በፍጹም ፡ ነፍስህም ፡ በፍጹም ፡ ኃይልህም ፡ በፍ ጹም ፡ አሳብህም ፡ ውደድ ፥ ባልንጀራህንም ፡ ፳፰፤ እንደ ፡ ራስህ ፡ ውደድ ፡ አለው ። ኢየሱስም ፦ እውነት ፡ መለስህ ፤ ይህን ፡ አድርግ ፡ በሕይወ ትም ፡ ትኖራ ለህ ፡ አለው ።

፳፱፤ እርሱ ፡ ግን ፡ ራሱን ፡ ሊያጸድቅ ፡ ወዶ ፡ ኢየ ሱስን ፦ ባልንጀራዬስ ፡ ማን ፡ ነው ? አለው ። ፴፤ ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ አንድ ፡ ሰው ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ኢያሪኮ ፡ ወረደ ፡ በወንበዴዎችም ፡ እጅ ፡ ወደቀ ፤ እነርሱም ፡ ደግሞ ፡ ገፈፉት ፡ ደበደቡትም ፡ በሕይወትና ፡ ፴፩፤ በሞት ፡ መካከልም ፡ ትተውት ፡ ሄዱ ። ድንገ ትም ፡ አንድ ፡ ካህን ፡ በዚያ ፡ መንገድ ፡ ወረደ ፡ ፴፪፤ አይቶትም ፡ ገለል ፡ ብሎ ፡ አለፈ ። እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ አንድ ፡ ሌዋዊ ፡ ወደዚያ ፡ ስፍራ ፡ ፴፫፤ መጣና ፡ አይቶት ፡ ገለል ፡ ብሎ ፡ አለፈ ። አንድ ፡ ሳምራዊ ፡ ግን ፡ ሲሄድ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጣ ፤ ፴፬፤ አይቶትም ፡ አዘነለት ፥ ቀርቦም ፡ ዘይትና ፡ የወ ይን ፡ ጠጅ ፡ በቍስሎቹ ፡ ላይ ፡ አፍስሶ ፡ አሰራ ቸው ፥ በራሱ ፡ አህያም ፡ ላይ ፡ አስቀምጦት ፡ ወደ ፡ እንግዶች ፡ ማደርያ ፡ወሰደው ፡ ጠበቀ ፴፭፤ ውም ። በማግሥቱም ፡ ሁለት ፡ ዲናር ፡ አው ጥቶ ፡ ለባለቤቱ ፡ ሰጠና ፦ ጠብቀው ፥ ከዚህም ፡ ዘላይ ፡ የምትከስረውን ፡ ሁሉ ፡ እኔ ፡ ስመለስ ፡ ፴፮፤ እከፍልሃለሁ ፡ አለው ። እንግዲህ ፡ ከነዚህ ፡ ከሦስቱ ፡ በወንበዴዎች ፡ እጅ ፡ ለወደቀው ፡ ባል ፴፯፤ ንጀራ ፡ የሆነው ፡ ማንኛው ፡ ይመስልሃል ? እር ሱም ፦ ምሕረት ፡ ያደረገለት ፡ አለ ። ኢየሱ ስም ፦ ሂድ ፡ አንተም ፡ እንዲሁ ፡ አድርግ ፡ አለው ።

፴፰፤ ሲሄዱም ፡ እርሱ ፡ ወደ ፡ አንዲት ፡ መንደር ፡ ገባ ፤ ማርታ ፡ የተባለች ፡ አንዲት ፡ሴትም ፡ በቤ ፴፱፤ ትዋ ፡ ተቀበለችው ። ለእርስዋም ፡ ማርያም ፡

፲። ፬፤ ምዕ. ፱ ፥ ፫ ። ፭፤ ምዕ. ፱ ፥ ፬ ። ፲፩፤ ምዕ. ፱ ፥ ፭ ። ፲፪ — ፲፭፤ ዘፍጥ. ፲፱ ፥ ፳፬ ፤ ማቴ. ፲ ፥ ፲፭ ፤ ፲፩ ፥ ፳፩ — ፳፬ ። ፲፮፤ ማቴ. ፲ ፥ ፵ ። ፲፰፤ ዮሐ. ፲፪ ፥ ፴፩ ። ፲፱፤ መዝ. ፺ ፥ ፲፫ ። ፳፤ ዘፀ. ፴፪ ፥ ፴፪ ፡ ወዘ ። ፳፩ ፡ ፳፪፤ ማቴ. ፲፩ ፥ ፳፭ — ፳፯ ፤ ዮሐ. ፫ ፥ ፴፭ ፤ ፲ ፥ ፲፭ ። ፳፫ ፡ ፳፬፤ ማቴ. ፲፫ ፥ ፲፮ ፡ ፲፯ ። ፳፭ — ፳፰፤ ማቴ. ፳፪ ፥ ፴፭ — ፵፩ ፤ ማር. ፲፪ ፥ ፳፰ — ፴፬ ። ፳፯፤ ዘዳግ. ፮ ፥ ፭ ፤ ዘሌዋ. ፲፱ ፥ ፲፰ ። ፳፰፤ ዘሌዋ. ፲፰ ፥ ፭ ። ፴፫፤ ዮሐ. ፬ ፥ ፱ ። ፴፰፤ ዮሐ. ፲፩ ፥ ፩ ።

የምትባል ፡ እኅት ፡ ነበረቻት ፤ እርስዋም ፡ ደግሞ ፡ ቃሉን ፡ ልትሰማ ፡ በኢየሱስ ፡ እግር ፡
፵ እጠገብ ፡ ተቀምጣ ፡ ነበረች ። ማርታ ፡ ግን ፡ አገልግሎት ፡ ስለ ፡ በዛባት ፡ ባከነች ፤ ቀርባም ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ እኅቴ ፡ እንድሠራ ፡ እኔን ፡ ብቻዬን ፡ ስትተወኝ ፡ አያገድህምን ? እንኪያስ ፡ እንድታግ
፵፩ ዘኝ ፡ ንገራት ፡ አለችው ። ኢየሱስም ፡ መለሰ ፦ ማርታ ፥ ማርታ ፥ በብዙ ፡ ነገር ፡ ትጨነቂአለሽ ፡
፵፪ ትታወኪማለሽ ፤ የሚያስፈልገው ፡ ግን ፡ ጥቂት ፡ ወይም ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ነው ፤ ማርያምም ፡ መል ካም ፡ ዕድልን ፡ መርጣለች ፡ ከእርስዋም ፡ አይ ወሰድባትም ፡ አላት ።

ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ እርሱም ፡ በአንድ ፡ ስፍራ ፡ ይጸልይ ፡ ነበር ፤ በጨረሰም ፡ ጊዜ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ አንዱ ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ዮሐንስ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ እንዳስተማረ ፡ እንጸልይ ፡ ዘንድ ፡ አስተምረን ፡
፪ አለው ። አላቸውም ፦ ስትጸልዩ ፡ እንዲህ ፡ በሉ ፦
በሰማያት ፡ የምትኖር ፡ አባታችን ፡ ሆይ ፤ ስምህ ፡ ይቀደስ ፤ መንግሥትህ ፡ ትምጣ ፤ ፈቃ ድህ ፡ በሰማይ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ እንዲሁ ፡ በምድር ፡
፫ ትሁን ፤ የዕለት ፡ እንጀራችንን ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡
፬ ስጠን ፤ ኃጢአታችንንም ፡ ይቅር ፡ በለን ፤ እኛ ፡ ደግሞ ፡ የበደሉንን ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡ ብለናልና ፤ ከክፉ ፡ አድነን ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ፈተና ፡ አታግ ባን ።
፭ እንዲህም ፡ አላቸው ፦ ከእናንተ ፡ ማናቸ ውም ፡ ወዳጅ ፡ ያለው ፥ በእኩል ፡ ሌሊትስ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ሄዶ ፦ ወዳጄ ፡ ሆይ ፥ ሦስት ፡
፮ እንጀራ ፡ አበድረኝ ፥ አንድ ፡ ወዳጄ ፡ ከመንገድ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጥቶ ፡ የማቀርብለት ፡ የለኝምና ፡
፯ ይላልን ? ያም ፡ ከውስጥ ፡ መልሶ ፦ አታድክ መኝ ፤ አሁን ፡ ደጁ ፡ ተቈልፎአል ፡ ልጆቼም ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ በአልጋ ፡ ላይ ፡ አሉ ፤ ተነሥቼ ፡
፰ ልሰጥህ ፡ አልችልም ፡ ይላልን ? እላችኋለሁ ፥ ወዳጁ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ተነሥቶ ፡ ባይሰጠው ፡ እንኳ ፥ ስለ ፡ ንዝነዛው ፡ ተነሥቶ ፡ የሚፈልገውን ፡
፱ ሁሉ ፡ ይሰጠዋል ። እኔም ፡ እላችኋለሁ ፦ ለምኑ ፥ ይሰጣችሁማል ፤ ፈልጉ ፥ ታገኙማላ ችሁ ፤ መዝጊያን ፡ አንኳኩ ፥ ይከፍትላችሁ
፲ ማል ። የሚለምን ፡ ሁሉ ፡ ይቀበላልና ፥ የሚፈ ልግም ፡ ያገኛል ፥ መዝጊያውንም ፡ ለሚያንኳ
፲፩ ኳው ፡ ይከፈትለታል ። አባት ፡ ከሆናችሁ ፡ ከእና ንተ ፡ ከማንኛችሁም ፡ ልጁ ፡ እንጀራ ፡ ቢለም ነው ፥ እርሱም ፡ ድንጋይ ፡ ይሰጠዋልን ? ዓሣ ፡ ደግሞ ፡ ቢለምነው ፡ በዓሣ ፡ ፋንታ ፡ እባብ ፡ ይሰጠ
፲፪ ዋልን ? ወይስ ፡ እንቍላል ፡ ቢለምነው ፡ ጊንጥ ፡
፲፫ ይሰጠዋልን ? እንኪያስ ፡ እናንተ ፡ ክፉዎች ፡ ስትሆኑ ፡ ለልጆቻችሁ ፡ መልካም ፡ ስጦታ ፡ መስ ጠት ፡ ካወቃችሁ ፥ በሰማይ ፡ ያለው ፡ አባት ፡ ለሚለምኑት ፡ እንዴት ፡ አብልጦ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ይሰጣቸው ?
፲፬ ዲዳውንም ፡ ጋኔን ፡ ያወጣ ፡ ነበር ፤ ጋኔኑም ፡ ከወጣ ፡ በኋላ ፡ ዲዳው ፡ ተናገረ ፤ ሕዝቡም ፡
፲፭ ተደነቁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከእነርሱ ፡ አንዳንዱ ፦ በብዔል ፡ ዜቡል ፡ በአጋንንት ፡ አለቃ ፡ አጋንን ትን ፡ ያወጣል ፡ አሉ ። ሌሎችም ፡ ሲፈትኑት ፡
፲፮ ከሰማይ ፡ ምልክት ፡ ከእርሱ ፡ ይፈልጉ ፡ ነበር ።
፲፯ እርሱ ፡ ግን ፡ አሳባቸውን ፡ አውቆ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ እርስ ፡ በርስዋ ፡ የምትለያይ ፡ መንግ ሥት ፡ ሁሉ ፡ ትጠፋለች ፤ ቤትም ፡ በቤት ፡ ላይ ፡ ይወ
፲፰ ድቃል ። እኔ ፡ አጋንንትን ፡ በብዔል ፡ ዜቡል ፡ እንዳወጣ ፡ ትላላችሁና ፡ ሰይጣን ፡ ደግሞ ፡ እርስ ፡ በርሱ ፡ ከተለያየ ፡ መንግሥቱ ፡ እንዴት ፡ ትቆ
፲፱ ማለች ? እኔስ ፡ በብዔል ፡ ዜቡል ፡ አጋንንትን ፡ የማወጣ ፡ ከሆንሁ ፥ ልጆቻችሁ ፡ በማን ፡ ያወጡ ኣቸዋል ? ስለዚህ ፡ እነርሱ ፡ ፈራጆች ፡ ይሆኑ
፳ ባችኋል ። እኔ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጣት ፡ አጋንንትን ፡ የማወጣ ፡ ከሆንሁ ፥ እንግዲህ ፡ የእ ግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ደር
፳፩ ሳለች ። ኃይለኛ ፡ ሰው ፡ ጋሻና ፡ ጦር ፡ ይዞ ፡ የራ ሱን ፡ ግቢ ፡ ሲጠብቅ ፥ ያለው ፡ ገንዘቡ ፡ በሰላም ፡
፳፪ ይሆናል ፤ ከእርሱ ፡ ይልቅ ፡ የሚበረታ ፡ መጥቶ ፡ ሲያሸንፈው ፡ ግን ፥ ታምኖበት ፡ የነበረውን ፡ ጋሻና ፡ ጦር ፡ ይወስድበታል ፡ ምርኮውንም ፡ ያከ
፳፫ ፋፍላል ። ከእኔ ፡ ጋር ፡ ያልሆነ ፡ ይቃወመኛል ፥ ከእኔ ፡ ጋርም ፡ የማያከማች ፡ ይበትናል ።
፳፬ ርኵስ ፡ መንፈስ ፡ ከሰው ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ዕረ ፍትን ፡ እየፈለገ ፡ ውኃ ፡ በሌለበት ፡ ቦታ ፡ ያል ፋል ፤ ባያገኝም ፦ ወደ ፡ ወጣሁበት ፡ ቤቴ ፡
፳፭ እመለሳለሁ ፡ ይላል ፤ ሲመጣም ፡ ተጠርጎ ፡ አጊ
፳፮ ጦም ፡ ያገኘዋል ። ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ይሄድና ፡ ከእርሱ ፡ የከፉትን ፡ ሌሎችን ፡ ሰባት ፡ አጋንንት ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይይዛል ፥ ገብተውም ፡ በዚያ ፡ ያድራሉ ፤ ስለዚያም ፡ ሰው ፡ ከፊተኛው ፡ ይልቅ ፡ የኋለኛው ፡ ይብስበታል ።
፳፯ ይህንም ፡ ሲናገር ፥ ከሕዝቡ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ድምፅዋን ፡ ከፍ ፡ አድርጋ ፦ የተሸከመችህ ፡ማኅ ፀንና ፡ የጠባሃቸው ፡ ጡቶች ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፡
፳፰ አለችው ። እርሱ ፡ ግን ፦ አዎን ፥ ብፁዓንስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ሰምተው ፡ የሚጠብ ቁት ፡ ናቸው ፡ አለ ።
፳፱ ብዙ ፡ ሕዝብም ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ ይል ፡ጀመር ፦ ይህ ፡ ትውልድ ፡ ክፉ ፡ ነው ፤ ምልክት ፡ ይፈልጋል ፥ ከነቢዩም ፡ ከዮናስ ፡ ምል
፴ ክት ፡ በቀር ፡ ምልክት ፡ አይሰጠውም ። ዮናስ ፡ ለነነዌ ፡ ሰዎች ፡ ምልክት ፡ እንደ ፡ ሆናቸው ፥ እንዲሁ ፡ ደግሞ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ለዚህ ፡ ትው

፲፩። ፳ ፤ ምሳ ፡ ፲፱ ። ፪—፱ ፤ ማቴ ፡ ፮ ፥ ፱—፲፫ ። ፰ ፤ ምሳ ፡ ፲፰ ፥ ፳—፯ ። ፱—፲፫ ፤ ማቴ ፡ ፯ ፥ ፯—፲፩ ፤ ማር ፡ ፲፩ ፥ ፳፬ ፤ ያዕ ፡ ፲፱ ፥ ፲፫ ። ፲፬ ፡ ፲፭ ፤ ማቴ ፡ ፲፪ ፥ ፳፪—፴፬ ፤ ማር ፡ ፫ ፥ ፳፪ ። ፲፮ ፤ ማቴ ፡ ፲፪ ፥ ፴፰ ። ፲፯—፳፪ ፤ ማቴ ፡ ፲፪ ፥ ፳፭—፳፱ ፤ ማር ፡ ፫ ፥ ፳፫—፳፯ ። ፳፫ ፤ ማቴ ፡ ፲፪ ፥ ፴ ። ፳፬—፳፮ ፤ ማቴ ፡ ፲፪ ፥ ፵፫—፵፭ ። ፳፰ ፤ ምሳ ፡ ፩ ፥ ፵፰ ። ፳፰ ፤ ምሳ ፡ ፰ ፥ ፳፩ ። ፳፱—፴፪ ፤ ማቴ ፡ ፲፪ ፥ ፴፱—፵፪ ። ፴ ፤ ዮና ፡ ፫ ፥ ፩—፲ ።

፴ ልጅ ፡ ምልክት ፡ ይሆናል ። ንግሥተ ፡ አዜብ ፡ በፍርድ ፡ ከዚህ ፡ ትውልድ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ተነሥታ ፡ ትፈርድባቸዋለች ፤ የሰሎሞንን ፡ ጥበብ ፡ ለመስማት ፡ ከምድር ፡ ዳር ፡ መጥታለችና ፥ እነሆም ፥ ከሰሎሞን ፡ የሚበልጥ ፡ ከዚህ ፡ አለ ።
፴፪ የነነዌ ፡ ሰዎች ፡ በፍርድ ፡ ከዚህ ፡ ትውልድ ፡ ጋር ፡ ተነሥተው ፡ ይፈርዱበታል ፤ በዮናስ ፡ ስብከት ፡ ንስሐ ፡ ገብተዋልና ፥ እነሆም ፥ ከዮናስ ፡ የሚበልጥ ፡ ከዚህ ፡ አለ ።
፴፫ መብራትንም ፡ አብርቶ ፡ በስውር ፡ ወይም ፡ በእንቅብ ፡ በታች ፡ የሚያኖረው ፡ የለም ፥ የሚገቡ ፡ ሰዎች ፡ ብርሃኑን ፡ እንዲያዩ ፡ በመቅረዝ ፡
፴፬ ላይ ፡ ያኖረዋል ፡ እንጂ ። የሰውነትህ ፡ መብራት ፡ ዓይንህ ፡ ናት ። ዓይንህ ፡ ጤናማ ፡ በሆነች ፡ ጊዜ ፡ ሰውነትህ ፡ ሁሉ ፡ ደግሞ ፡ ብሩህ ፡ ይሆናል ። ዓይንህ ፡ ታማሚ ፡ በሆነች ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ሰውነ
፴፭ ትህ ፡ ደግሞ ፡ የጨለመ ፡ ይሆናል ። እንግዲህ ፡ በአንተ ፡ ያለው ፡ ብርሃን ፡ ጨለማ ፡ እንዳይሆን ፡
፴፮ ተመልከት ። እንግዲህ ፡ ሰውነትህ ፡ ሁሉ ፡ የጨለማ ፡ ቍራጭ ፡ የሌለበት ፡ ብሩህ ፡ ቢሆን ፥ መብራት ፡ በደመቀ ፡ ብርሃን ፡ እንደሚያበራልህ ፡ በሞላው ፡ ብሩህ ፡ ይሆናል ።
፴፯ ይህንንም ፡ ሲናገር ፡ አንድ ፡ ፈሪሳዊ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ምሳ ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ ለመነው ፤ ገብቶም ፡
፴፰ ተቀመጠ ። ከምሳም ፡ በፊት ፡ አስቀድሞ ፡ እንዳልታጠበ ፡ ባየው ፡ ጊዜ ፡ ፈሪሳዊው ፡ ተደነቀ ።
፴፱ ጌታም ፡ እንዲህ ፡ አለው ፦ አሁን ፡ እናንተ ፡ ፈሪሳውያን ፡ የጽዋውንና ፡ የወጭቱን ፡ ውጭ ፡ ታጠራላችሁ ፥ ውስጣችሁ ፡ ግን ፡ ቅሚያና ፡
፵ ክፋት ፡ ሞልቶበታል ። እናንተ ፡ ደንቆሮዎች ፥ የውጭውን ፡ የፈጠረ ፡ የውስጡን ፡ ደግሞ ፡ አል
፵፩ ፈጠረምን ? ነገር ፡ ግን ፡ በውስጥ ፡ ያለውን ፡ ምጽዋት ፡ አድርጋችሁ ፡ ስጡ ፥ እነሆም ፥ ሁሉ ፡ ንጹሕ ፡ ይሆንላችኋል ።
፵፪ ነገር ፡ ግን ፡ እናንተ ፡ ፈሪሳውያን ፥ ከእንስላልና ፡ ከጤና ፡ አዳም ፡ ከአትክልትም ፡ ሁሉ ፡ አሥራት ፡ ስለምታወጡ ፥ ፍርድንና ፡ እግዚአብሔርን ፡ መውደድ ፡ ስለምትተላለፉ ፥ ወዮላችሁ ! ነገር ፡ ግን ፡ ሌላውን ፡ ሳትተዉ ፡ ይህን ፡ ልታ
፵፫ ደርጉት ፡ ይገባችሁ ፡ ነበር ። እናንተ ፡ ፈሪሳውያን ፥ በምኵራብ ፡ የከበሬታ ፡ ወንበር ፡ በገበ
፵፬ ያም ፡ ሰላምታ ፡ ስለምትወዱ ፥ ወዮላችሁ ። እናንተ ፡ግብዞች ፡ ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያን ፥ ሰዎች ፡ ሳያውቁ ፡ በላዩ ፡ የሚሄዱበት ፡ የተሰወረ ፡ መቃብር ፡ ስለምትመስሉ ፥ ወዮላችሁ ።
፵፭ ከሕግ ፡ አዋቂዎችም ፡ አንዱ ፡ መልሶ ፦ መምህር ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ማለትህ ፡ እኛን ፡ ደግሞ ፡ መስደ
፵፮ ብህ ፡ ነው ፡ አለው ። እርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ሕግ ፡ አዋቂዎች ፥ አስቸጋሪ ፡ ሸክም ፡ ለሰዎች ፡ ስለምታሸክሙ ፥ ራሳችሁም ፡ በአንዲት ፡ ጣታችሁ ፡ ስንኳ ፡ ሸክሙን ፡ ስለማ
፵፯ ትነኩት ፥ ወዮላችሁ ። አባቶቻችሁ ፡ የገደሉ አቸውን ፡ የነቢያትን ፡ መቃብር ፡ ስለምትሠሩ ፥
፵፰ ወዮላችሁ ። እንግዲህ ፡ ለአባቶቻችሁ ፡ ሥራ ፡ ትመሰክራላችሁ ፡ ትስማማላችሁም ፤ እነርሱ ፡ ገድለዋቸዋልና ፥ እናንተም ፡ መቃብራቸውን ፡
፵፱ ትሠራላችሁ ። ስለዚህ ፡ ደግሞ ፡ የእግዚአብ ሔር ፡ ጥበብ ፡ እንዲህ ፡ አለች ፦ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ነቢያትንና ፡ ሐዋርያትን ፡ እልካለሁ ፥ ከእነር ሱም ፡ ይገድላሉ ፡ ያሳድዱማል ፥ ዓለም ፡ ከተ
፶ ፈጠረ ፡ ጀምሮ ፡ የፈሰሰው ፡ የነቢያት ፡ ሁሉ ፡
፶፩ ደም ፥ ከአቤል ፡ ደም ፡ ጀምሮ ፡ በመሠዊያውና ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ መካከል ፡ እስከ ፡ ጠፋው ፡ እስከ ፡ ዘካርያስ ፡ ደም ፡ ድረስ ፥ ከዚህ ፡ ትውልድ ፡ እንዲፈለግ ፤ አዎን ፡ እላችኋለሁ ፥ ከዚህ ፡
፶፪ ትውልድ ፡ ይፈለጋል ። እናንተ ፡ ሕግ ፡ አዋቂ ዎች ፥ የእውቀትን ፡ መክፈቻ ፡ ስለ ፡ ወሰዳችሁ ፥ ወዮላችሁ ፤ ራሳችሁ ፡ አልገባችሁም ፡ የሚገ ቡትንም ፡ ከለከላችሁ ።
፶፫፡፶፬ ይህንም ፡ሲናገራቸው ፥ ጻፎችና ፡ ፈሪሳው ያን ፡ በአፉ ፡ የተናገረውን ፡ ሊነጥቁ ፡ ሲያደቡ ፥ እጅግ ፡ ይቃወሙና ፡ ስለ ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ እንዲና ገር ፡ ያነሣሡ ፡ ጀመር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የሕዝብ ፡ አእላፍ ፡ እርስ ፡ በር ሳቸው ፡ እስኪረጋገጡ ፡ ድረስ ፡ ተሰብስበው ፡ ሳሉ ፥ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ እንዲህ ፡ ይል ፡ ጀመር ፦ አስቀድማችሁ ፡ ከፈሪሳውያን ፡ እርሾ ፡
፪ ተጠበቁ ፥ እርሱም ፡ግብዝነት ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ የማይገለጥ ፡ የተከደነ ፥ የማይታወቅም ፡
፫ የተሰወረ ፡ ምንም ፡ የለም ። ስለዚህ ፡ በጨለማ ፡ የምትናገሩት ፡ ሁሉ ፡ በብርሃን ፡ ይሰማል ፥ በእ ልፍኝም ፡ ውስጥ ፡ በጆሮ ፡ የምትናገሩት ፡ በሰ ገነት ፡ ላይ ፡ ይሰበካል ።
፬ ለእናንተም ፡ለወዳጆቼ ፡ እላችኋለሁ ፥ ሥጋን ፡ የሚገድሉትን ፡ በኋላም ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ የሚ በልጥ ፡ ሊያደርጉ ፡ የማይችሉትን ፡ አትፍሩ ።
፭ እኔ ፡ ግን ፡ የምትፈሩትን ፡ አሳያችኋለሁ ፤ ከገ ደለ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ለመጣል ፡ ሥል ጣን ፡ ያለውን ፡ ፍሩ ። አዎን ፡ እላችኋለሁ ፥ እር
፮ ሱን ፡ ፍሩ ። አምስት ፡ ድንቢጦች ፡ በአሥር ፡ ሳንቲም ፡ ይሸጡ ፡ የለምን ? ከእነርሱም ፡ አን
፯ ዲቱ ፡ ስንኳ ፡ በእግዚአብሔር ፡ፊት ፡ አትረሳም ። ነገር ፡ ግን ፡ የእናንተ ፡ የራሳችሁ ፡ ጠጕር ፡ ሁሉ ፡ እንኳ ፡ የተቈጠረ ፡ ነው ፤ እንግዲያስ ፡ አትፍሩ ፤ ከብዙ ፡ ድንቢጦች ፡ ትበልጣላችሁ ።
፰ እላችሁማለሁ ፥ በሰው ፡ ፊት ፡ የሚመሰክር ልኝ ፡ ሁሉ ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ ደግሞ ፡ በእግዚአ ብሔር ፡ መላእክት ፡ ፊት ፡ ይመሰክርለታል ፤

፲፩ ። ፴፩ ፤ ፩ ነገሥ. ፲ ፥ ፩ ። ፴፪ ፤ ዮና. ፫ ፥ ፭ ። ፴፫ ፤ ም. ፭ ፥ ፲፭ ። ፴፬ ፡ ፴፭ ፤ ማቴ. ፮ ፥ ፳፪ ፡ ፳፫ ። ፴፯ ፤ ማቴ. ፲፭ ፥ ፪ ።
፴፱ ፤ ማቴ. ፳፫ ፥ ፳፭ ። ፵፪ ፤ ማቴ. ፳፫ ፥ ፳፫ ። ፵፫ ፤ ም. ፳ ፥ ፵፮ ፤ ማቴ. ፳፫ ፥ ፮ ፡ ፯ ። ፵፬ ፤ ማቴ. ፳፫ ፥ ፳፯ ።
፵፯ ፡ ፵፰ ፤ ማቴ. ፳፫ ፥ ፳፱ — ፴፩ ። ፵፱ — ፶፩ ፤ ማቴ. ፳፫ ፥ ፴፬ — ፴፮ ። ፶፪ ፤ ማቴ. ፳፫ ፥ ፲፫ ። [illegible] ፤ ም. ፳ ፥ ፳ ።
፲፪ ። ፩ ፤ ማቴ. ፲፮ ፥ ፮ ። ፪ — ፱ ፤ ማቴ. ፲ ፥ ፳፮ — ፴፫ ። ፪ ፤ ም. ፰ ፥ ፲፯ ። ፯ ፤ ማቴ. ፯ ፥ [illegible] ።

፱ በሰውም ፡ ፊት ፡ የሚክደኝ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፲ መላእክት ፡ ፊት ፡ ይካዳል ። በሰው ፡ ልጅም ፡ ላይ ፡ ቃል ፡ የሚናገር ፡ ሁሉ ፡ ይሰረይለታል ፤ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ የሚሰድብ ፡ ግን ፡ አይሰረይ ፲፩ ለትም ። ወደ ፡ ምኵራቦችና ፡ ወደ ፡ መኳንን ቶችም ፡ ወደ ፡ ገዢዎችም ፡ ሲጐትቱአችሁ ፥ እንዴት ፡ ወይም ፡ ምን ፡ እንድትመልሱ ፡ ወይም ፲፪ እንድትናገሩ ፡ አትጨነቁ ፤ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በዚያች ፡ ሰዓት ፡ ልትናገሩት ፡ የሚገባችሁን ፡ ያስተምራችኋልና ።

፲፫ ከሕዝቡም ፡ አንድ ፡ ሰው ፦ መምህር ፡ ሆይ ፥ ርስቱን ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ እንዲካፈል ፡ ለወንድሜ ፡ ፲፬ ንገረው ፡ አለው ። እርሱም ፦ አንተ ፡ ሰው ፥ ፈራጅና ፡ አካፋይ ፡ በላያችሁ ፡ እንድሆን ፡ ማን ፡ ፲፭ ሾመኝ ? አለው ። የሰው ፡ ሕይወት ፡ በገንዘቡ ፡ ብዛት ፡ አይደለምና ፡ ተጠንቀቁ ፥ ከመጐምጀ ፲፮ ትም ፡ ሁሉ ፡ ተጠበቁ ፡ አላቸው ። ምሳሌም ፡ ነገራቸው ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፦ አንድ ፡ ባለ ፡ ጠጋ ፡ ሰው ፡ እርሻ ፡ እጅግ ፡ ፍሬያም ፡ ሆነችለት ። ፲፯ እርሱም ፦ ፍሬዬን ፡ የማከማችበት ፡ ስፍራ ፡ አጥቻለሁና ፡ ምን ፡ ላድርግ ? ብሎ ፡ በልቡ ፡ ፲፰ አሰበ ። እንዲህ ፡ አደርጋለሁ ፤ ጐተራዬን ፡ አፍርሼ ፡ ሌላ ፡ የሚበልጥ ፡ እሠራለሁ ፥ በዚያም ፡ ፍሬዬንና ፡ በረከቴን ፡ ሁሉ ፡ አከማቻለሁ ፤ ፲፱ ነፍሴንም ፦ አንቺ ፡ ነፍሴ ፥ ለብዙ ፡ ዘመን ፡ የሚቀር ፡ ብዙ ፡ በረከት ፡ አለሽ ፤ ዕረፊ ፥ ብዪ ፥ ፳ ጠጪ ፥ ደስ ፡ ይበልሽ ፡ እላታለሁ ፡ አለ ። እግዚአ ብሔር ፡ ግን ፦ አንተ ፡ ሰነፍ ፥ በዚች ፡ ሌሊት ፡ ነፍስህን ፡ ከአንተ ፡ ሊወስዱአት ፡ ይፈልጓታል ፤ ይህስ ፡ የሰበሰብኸው ፡ ለማን ፡ ይሆናል ? አለው ። ፳፩ ለራሱ ፡ ገንዘብ ፡ የሚያከማች ፥ ለእግዚአብሔር ፡ ዘንድም ፡ ባለ ፡ ጠጋ ፡ ያልሆነ ፡ እንዲህ ፡ ነው ።

፳፪ ለደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ ስለ ዚህ ፡ እላችኋለሁ ፥ ለነፍሳችሁ ፡ በምትበሉት ፡ ወይም ፡ ለሰውነታችሁ ፡ በምትለብሱት ፡ አት ፳፫ ጨነቁ ። ነፍስ ፡ ከመብል ፡ ሰውነትም ፡ ከልብስ ፡ ፳፬ ይበልጣልና ። ቍራዎችን ፡ ተመልከቱ ፤ አይ ዘሩም ፡ አያጭዱምም ፥ ዕቃ ፡ ቤትም ፡ ወይም ፡ ጎተራ ፡ የላቸውም ፥ እግዚአብሔርም ፡ ይመግ ባቸዋል ፤ እናንተስ ፡ ከወፎች ፡ እንዴት ፡ ትበ ፳፭ ልጣላችሁ ? ከእናንተ ፡ ተጨንቆ ፡ በቁመቱ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ክንድ ፡ መጨመር ፡ የሚችል ፡ ማን ፡ ፳፮ ነው ? እንግዲህ ፡ ትንሹን ፡ ነገር ፡ ስንኳ ፡ የማ ትችሉ ፡ ከሆናችሁ ፥ ስለ ፡ ምን ፡ በሌላ ፡ ትጨነ ፳፯ ቃላችሁ ? አበቦችን ፡ እንዴት ፡ እንዲያድጉ ፡ ተመልከቱ ፤ አይደክሙም ፡ አይፈትሉምም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ፥ ሰሎሞንስ ፡ እንኳ ፡ በክ ብሩ ፡ ሁሉ ፡ ከእነዚህ ፡ እንደ ፡ አንዲቱ ፡ አልለበ ፳፰ ሰም ። እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ዛሬ ፡ ያለውን ፡ ነገም ፡ ወደ ፡ እቶን ፡ የሚጣለውን ፡ በሜዳ ፡ የሆ ነውን ፡ ሣር ፡ እንዲህ ፡ የሚያስጌጠው ፡ ከሆነ ፥ እናንተ ፡ እምነት ፡ የጐደላችሁ ፥ እናንተንማ ፡ ፳፱ ይልቁን ፡ እንዴት ? እናንተም ፡ የምትበሉትን ፡ የምትጠጡትንም ፡ አትፈልጉ ፥ አታወላው ፴ ሉም ፤ ይህንስ ፡ ሁሉ ፡ በዓለም ፡ ያሉ ፡ አሕዛብ ፡ ይፈልጉታልና ፤ የእናንተም ፡ አባት ፡ ይህ ፡ እን ፴፩ ዲያስፈልጋችሁ ፡ ያውቃል ። ዳሩ ፡ ግን ፡ መን ግሥቱን ፡ ፈልጉ ፡ ይህም ፡ ሁሉ ፡ ይጨመርላ ችኋል ።

፴፪ አንተ ፡ ታናሽ ፡ መንጋ ፥ መንግሥትን ፡ ሊሰ ጣችሁ ፡ የአባታችሁ ፡ በጎ ፡ ፈቃድ ፡ ነውና ፡ አት ፴፫ ፍሩ ። ያላችሁን ፡ሽጡ ፡ ምጽዋትም ፡ ስጡ ፤ ሌባ ፡ በማይቀርብበት ፡ ብልም ፡ በማያጠፋበት ፡ በሰማያት ፡ የማያልቅ ፡ መዝገብ ፡ የሚሆኑትን ፡ የማያረጁትንም ፡ ኮረጆዎች ፡ ለራሳችሁ ፡ አድ ፴፬ ርጉ ፤ መዝገባችሁ ፡ ባለበት ፡ ልባችሁ ፡ ደግሞ ፡ በዚያ ፡ ይሆናልና ።

፴፭ ወገባችሁ ፡ የታጠቀ ፡ መብራታችሁም ፡ ፴፮ የበራ ፡ ይሁን ፤ እናንተም ፡ ጌታቸው ፡ መጥቶ ፡ ደጁን ፡ ሲያንኳኳ ፡ ወዲያው ፡ እንዲከፍቱለት ፡ ከሰርግ ፡ እስኪመለስ ፡ ድረስ ፡ የሚጠብቁ ፡ ሰዎ ፴፯ ችን ፡ ምሰሉ ። ጌታቸው ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ሲተጉ ፡ የሚ ያገኛቸው ፡ እነዚያ ፡ ባሪያዎች ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፤ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ታጥቆ ፡ በማዕድ ፡ ያስቀ ፴፰ ምጣቸዋል ፡ ቀርቦም ፡ ያገለግላቸዋል ። ከሌሊ ቱም ፡ በሁለተኛው ፡ ወይም ፡ በሦስተኛው ፡ ክፍል ፡ መጥቶ ፡ እንዲሁ ፡ ቢያገኛቸው ፥ እነዚያ ፡ ፴፱ ባሪያዎች ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ። ይህን ፡ ግን ፡ እወቁ ፤ ባለቤት ፡ በምን ፡ ሰዓት ፡ ሌባ ፡ እንዲመጣ ፡ ቢያ ውቅ ፡ ኖሮ ፥ በነቃ ፥ ቤቱም ፡ እንዲቆፈር ፡ ባል ፵ ፈቀደም ፡ ነበር ። እናንተ ፡ ደግሞ ፡ተዘጋጅታ ችሁ ፡ ኑሩ ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ በማታስቡበት ፡ ሰዓት ፡ ይመጣልና ።

፵፩ ጴጥሮስም ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ ምሳሌ ፡ ለእኛ ፡ ወይስ ፡ ደግሞ ፡ ለሁሉ ፡ ትናገራለህን ? ፵፪ አለው ። ጌታም ፡ አለ ፦ እንኪያስ ፡ ምግባቸ ውን ፡ በጊዜው ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ጌታው ፡ በቤተ ፡ ሰዎቹ ፡ ላይ ፡ የሚሾመው ፡ ታማኝና ፡ ፵፫ ልባም ፡ መጋቢ ፡ ማን ፡ ነው ? ጌታው ፡ መጥቶ ፡ እንዲህ ፡ ሲያደርግ ፡ የሚያገኘው ፡ ያ ፡ ባሪያ ፡ ፵፬ ብፁዕ ፡ ነው ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ባለው ፡ ፵፭ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ይሾመዋል ። ያ ፡ ባሪያ ፡ ግን ፦ ጌታዬ ፡ እስኪመጣ ፡ ይዘገያል ፡ ብሎ ፡ በልቡ ፡ ቢያ ስብ ፡ ሎሌዎችንና ፡ ገረዶችንም ፡ ይመታ ፡ ይበ ላም ፡ ይጠጣም ፡ ይሰክርም ፡ ዘንድ ፡ ቢጀምር ፥ ፵፮ የዚያ ፡ ባሪያ ፡ ጌታ ፡ ባልጠበቃት ፡ ቀን ፡ ባላወ ቃትም ፡ ሰዓት ፡ ይመጣል ፥ ከሁለትም ፡ ይሰነጥ ቀዋል ፡ እድሉንም ፡ ከማይታመኑ ፡ ጋር ፡ ያደር ፵፯ ጋል ። የጌታውንም ፡ ፈቃድ ፡ አውቆ ፡ ያልተ ዘጋጀ ፡ እንደ ፡ ፈቃዱም ፡ ያላደረገ ፡ ያ ፡ ባሪያ ፡

፲፪ ። ፪ ፤ ም. ፪ ፥ ፳፪ ። ፲ ፤ ማቴ. ፲፪ ፥ ፴፪ ፤ ማር. ፫ ፥ ፳፱ ። ፲፩ ፡ ፲፪ ፤ ም. ፳፩ ፥ ፲፬ – ፲፭ ፤ ማቴ. ፲ ፥ ፲፱ – ፳ ። ፳ ፤ መዝ. ፶፪ ፥ ፯ ። ፳፩ ፤ ማቴ. ፮ ፥ ፲፱ ። ፳፪—፴፩ ፤ ማቴ. ፮ ፥ ፳፭—፴፫ ። ፴፪ ፤ ም. ፳፪ ፥ ፳፱ ። ፴፫ ፡ ፴፬ ፤ ማቴ. ፮ ፥ ፲፱—፳፩ ። ፴፭ ፡ ፴፮ ፤ ማቴ. ፳፭ ፥ ፩—፲፫ ። ፴፯ ፤ ማቴ. ፳፬ ፥ ፵፮ ፤ ማር. ፲፫ ፥ ፴፬ ፡ ፴፭ ። ፴፱—፵፮ ፤ ማቴ. ፳፬ ፥ ፵፫—፶፩ ።

፵፰ እጅግ ፡ ይገረፋል ፤ ያላወቀ ፡ ግን ፡ መገረፍ ፡ የሚገባውንም ፡ ያደረገ ፡ ጥቂት ፡ ይገረፋል ። ብዙም ፡ ከተሰጠው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ ብዙ ፡ ይፈለግበታል ፥ ብዙ ፡ አደራም ፡ ከተሰጠው ፡ ከእርሱ ፡ አብዝተው ፡ ይሹበታል ።

፵፱ በምድር ፡ ላይ ፡ እሳት ፡ ልጥል ፡ መጣሁ ፥ አሁንም ፡ የነደደ ፡ ከሆነ ፡ ሀንድ ፡ ምን ፡ እፈልጋለሁ ? ፶ ነገር ፡ ግን ፡ የምጠመቃት ፡ ጥምቀት ፡ አለችኝ ፥ እስክትፈጸምም ፡ ድረስ ፡ እንዴት ፡ እጨነቃለሁ ? ፶፩ በምድር ፡ ላይ ፡ ሰላምን ፡ ለመስጠት ፡ የመጣሁ ፡ ይመስላችኋልን ? እላችኋለሁ ፥ አይደለም ፥ መለያየትን ፡ እንጂ ። ፶፪ ከአሁን ፡ ጀምሮ ፡ በአንዲት ፡ ቤት ፡ አምስት ፡ ሰዎች ፡ ይኖራሉና ፤ ሦስቱም ፡ በሁለቱ ፡ ላይ ፡ ሁለቱም ፡ በሦስቱ ፡ ላይ ፡ ተነሥተው ፡ ይለያያሉ ። ፶፫ አባት ፡ በልጁ ፡ ላይ ፡ ልጅም ፡ በአባቱ ፡ ላይ ፥ እናት ፡ በልጅዋ ፡ ላይ ፡ ልጅዋም ፡ በእናትዋ ፡ ላይ ፥ አማት ፡ በምራትዋ ፡ ላይ ፡ ምራትም ፡ በአማትዋ ፡ ላይ ፡ ተነሥተው ፡ ይለያያሉ ።

፶፬ ደግሞም ፡ ሕዝቡን ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ ደመና ፡ ከምዕራብ ፡ ሲወጣ ፡ ባያችሁ ፡ ጊዜ ፥ ወዲያው ፦ ዝናብ ፡ ይመጣል ፡ ትላላችሁ ፥ እንዲሁም ፡ ይሆናል ፤ ፶፭ በአዜብም ፡ ነፋስ ፡ ሲነፍስ ፦ ትኩሳት ፡ ይሆናል ፡ ትላላችሁ ፥ ይሆንማል ። ፶፮ እናንተ ፡ ግብዞች ፥ የምድሩንና ፡ የሰማዩን ፡ ፊት ፡ ልትመረምሩ ፡ ታውቃላችሁ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ይህን ፡ ዘመን ፡ የማትመረምሩ ፡ እንዴት ፡ ነው ?

፶፯ ራሳችሁ ፡ ደግሞ ፡ ጽድቅን ፡ የማትፈርዱ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ነው ? ፶፰ ከባላጋራህ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ሹም ፡ ብትሄድ ፥ ወደ ፡ ዳኛ ፡ እንዳይጐትትህ ፡ ዳኛውም ፡ ለሎሌው ፡ አሳልፎ ፡ እንዳይሰጥህ ፡ ሎሌውም ፡ በወኅኒ ፡ እንዳይጥልህ ፥ ገና ፡ በመንገድ ፡ ሳለህ ፡ ከባላጋራህ ፡ እንድትታረቅ ፡ ትጋ ። ፶፱ እልሃለሁ ፥ የመጨረሻዋን ፡ ግማሽ ፡ ሳንቲም ፡ እስክትከፍል ፡ ድረስ ፡ ከዚያ ፡ ከቶ ፡ አትወጣም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ሰዎች ፡ መጥተው ፡ ጲላጦስ ፡ ደማቸውን ፡ ከመሥዋዕታቸው ፡ ጋር ፡ ስላደባለቀው ፡ ስለ ፡ ገሊላ ፡ ሰዎች ፡ አወሩለት ። ፪ ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ እንዚህ ፡ የገሊላ ፡ ሰዎች ፡ ይህ ፡ ስለ ፡ ደረሰባቸው ፡ ከገሊላ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ኃጢአተኞች ፡ የሆኑ ፡ ይመስሉአችኋልን ? ፫ እላችኋለሁ ፥ አይደለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ንስሐ ፡ ባትገቡ ፡ ሁላችሁ ፡ እንዲሁ ፡ ትጠፋላችሁ ። ፬ ወይስ ፡ በሰሊሆም ፡ ግንቡ ፡ የወደቀባቸውና ፡ የገደላቸው ፡ እነዚያ ፡ አሥራ ፡ ስምንት ፡ ሰዎች ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ከሚኖሩት ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ በደለኞች ፡ ይመስሉአችኋልን ? ፭ አይደለም ፥ እላችኋለሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ንስሐ ፡ ባትገቡ ፡ ሁላችሁ ፡ እንደዚሁ ፡ ትጠፋላችሁ ።

፮ ይህንም ፡ ምሳሌ ፡ አለ ፦ ለአንድ ፡ ሰው ፡ በወይኑ ፡ አትክልት ፡ የተተከለች ፡ በለስ ፡ ነበረችው ፥ ፍሬም ፡ ሊፈልግባት ፡ መጥቶ ፡ ምንም ፡ አላገኘም ። ፯ የወይን ፡ አትክልት ፡ ሠራተኛውንም ፦ እነሆ ፥ ከዚህች ፡ በለስ ፡ ፍሬ ፡ ልፈልግ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ እየመጣሁ ፡ ምንም ፡ አላገኘሁም ፤ ቍረጣት ፤ ስለ ፡ ምን ፡ ደግሞ ፡ መሬቱን ፡ ታጐሰቍላለች ? አለው ። ፰ እርሱ ፡ ግን ፡ መልሶ ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ዙሪያዋን ፡ እስክኰተኵትላትና ፡ ፋንድያ ፡ እስክፈስላት ፡ ድረስ ፡ በዚች ፡ ዓመት ፡ ደግሞ ፡ ተዋት ። ፱ ወደ ፡ ፊትም ፡ ብታፈራ ፥ ደኅና ፡ ነው ፤ ያለዚያ ፡ ግን ፡ ትቈርጣታለህ ፡ አለው ።

፲ በሰንበትም ፡ በአንድ ፡ ምኵራብ ፡ ያስተምር ፡ ነበር ። ፲፩ እነሆም ፥ ከአሥራ ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ የድካም ፡ መንፈስ ፡ ያደረባት ፡ ሴት ፡ ነበረች ፥ እርስዋም ፡ ጐባጣ ፡ ነበረች ፡ ቀንታም ፡ ልትቆም ፡ ከቶ ፡ አልተቻላትም ። ፲፪ ኢየሱስም ፡ ባያት ፡ ጊዜ ፡ ጠራትና ፦ አንቺ ፡ ሴት ፥ ከድካምሽ ፡ ተፈትተሻል ፡ አላት ፥ ፲፫ እጁንም ፡ ጫነባት ፤ ያን ፡ ጊዜም ፡ ቀጥ ፡ አለች ፥ እግዚአብሔርንም ፡ አመሰገነች ። ፲፬ የምኵራብ ፡ አለቃ ፡ ግን ፡ ኢየሱስ ፡ በሰንበት ፡ ስለ ፡ ፈወሰ ፡ ተቈጥቶ ፡ መለሰና ፡ ሕዝቡን ፦ ሊሠራባቸው ፡ የሚገባ ፡ ስድስት ፡ ቀኖች ፡ አሉ ፤ እንግዲህ ፡ በእነርሱ ፡ መጥታችሁ ፡ ተፈወሱ ፡ እንጂ ፡ በሰንበት ፡ አይደለም ፡ አለ ። ፲፭ ጌታም ፡ መልሶ ፦ እናንተ ፡ ግብዞች ፥ ከእናንተ ፡ እያንዳንዱ ፡ በሰንበት ፡ በሬውን ፡ ወይስ ፡ አህያውን ፡ ከግርግም ፡ ፈትቶ ፡ ውኃ ፡ ሊያጠጣው ፡ ይወስደው ፡ የለምን ? ፲፮ ይህችም ፡ የአብርሃም ፡ ልጅ ፡ ሆና ፡ ከአሥራ ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ሰይጣን ፡ ያሰራት ፡ በሰንበት ፡ ቀን ፡ ከዚህ ፡ እስራት ፡ ልትፈታ ፡ አይገባምን ? አለው ። ፲፯ ይህንም ፡ ሲናገር ፡ ሳለ ፡ የተቃወሙት ፡ ሁሉ ፡ አፈሩ ፤ ከእርሱም ፡ በተደረገው ፡ ድንቅ ፡ ሁሉ ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ አላቸው ።

፲፰ እርሱም ፦ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ምን ፡ ትመስላለች ፥ በምንስ ፡ አስመስላታለሁ ? ፲፱ ሰው ፡ ወስዶ ፡ በአትክልቱ ፡ የጣላትን ፡ የሰናፍጭ ፡ ቅንጣት ፡ ትመስላለች ፤ አደገችም ፡ ታላቅ ፡ ዛፍም ፡ ሆነች ፥ የሰማይ ፡ ወፎችም ፡ በቅርንጫፎችዋ ፡ ሰፈሩ ፡ አለ ።

፳ ደግሞም ፥ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ በምን ፡ አስመስላታለሁ ? ፳፩ ሴት ፡ ወስዳ ፡ ሁሉ ፡ እስኪቦካ ፡ ድረስ ፡ በሦስት ፡ መስፈሪያ ፡ ዱቄት ፡ የሸሸገችውን ፡ እርሾ ፡ ትመስላለች ፡ አለ ።

፳፪ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ሲሄድ ፡ ከተማዎችንና ፡ መንደሮችን ፡ እያስተማረ ፡ ያልፍ ፡ ነበር ።

፲፪። ፶፤ ማቴ. ፳ ፥ ፳፪። ፶፩—፶፫፤ ማቴ. ፲ ፥ ፴፬—፴፮። ፶፫፤ ሚክ. ፯ ፥ ፮። ፶፬—፶፮፤ ማቴ. ፲፮ ፥ ፪, ፫። ፶፰, ፶፱፤ ማቴ. ፭ ፥ ፳፭, ፳፮።

፲፫። ፮፤ ዮሐ. ፲፭ ፥ ፪። ፯፤ ማቴ. ፫ ፥ ፲። ፱፤ ማቴ. ፯ ፥ ፲፱። ፲፬፤ ዘፀአ. ፳ ፥ ፱። ፲፭፤ ም. ፲፬ ፥ ፭። ፲፰, ፲፱፤ ማቴ. ፲፫ ፥ ፴፩, ፴፪፤ ማር. ፬ ፥ ፴—፴፪። ፳, ፳፩፤ ማቴ. ፲፫ ፥ ፴፫። ፳፪፤ ም. ፱ ፥ ፶፩።

፳፫ አንድ ፡ ሰውም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ የሚድኑ ፡ ጥቂ ቶች ፡ ናቸውን ? አለው ። እርሱም ፡ እንዲህ ፡ ፳፬ አላቸው ፡— በጠበበው ፡ በር ፡ ለመግባት ፡ ተጋ ደሉ ፤ እላችኋለሁና ÷ ብዙዎች ፡ ሊገቡ ፡ ይፈ ፳፭ ልጋሉ ፡ አይችሉምም ። ባለቤቱ ፡ ተነሥቶ ፡ በሩን ፡ ከቈለፈ ፡ በኋላ ÷ እናንተ ፡ በውጭ ፡ ቆማ ችሁ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ ጌታ ፡ ሆይ ÷ ክፈትልን ፡ እያላችሁ ፡ በሩን ፡ ልታንኳኩ ፡ ትጀምራላችሁ ፤ እርሱም ፡ መልሶ ፡— ከወዴት ፡ እንደ ፡ ሆና ፳፮ ችሁ ፡ አላውቃችሁም ፡ ይላችኋል ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡— በፊትህ ፡ በላን ፡ ጠጣንም ፡ በአደባባ ያችንም ፡ አስተማርህ ፡ ልትሉ ፡ ትጀምራላችሁ ፤ ፳፯ እርሱም ፡— እላችኋለሁ ÷ ከወዴት ፡ እንደ ፡ ሆና ችሁ ፡ አላውቃችሁም ፤ ሁላችሁ ፡ ዓመፀኞች ÷ ፳፰ ከእኔ ፡ ራቁ ፡ ይላችኋል ። አብርሃምንና ፡ ይስሐ ቅን ፡ ያዕቆብንም ፡ ነቢያትንም ፡ ሁሉ ፡ በእግዚ አብሔር ፡ መንግሥት ፡ ባያችሁ ፡ ጊዜ ÷ እናንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ተጥላችሁ ፡ ስትቀሩ ÷ በዚያ ፡ ፳፱ ልቅሶና ፡ ጥርስ ፡ ማፋጨት ፡ ይሆናል ። ከምሥ ራቅና ፡ ከምዕራብም ፡ ከሰሜንና ፡ ከደቡብም ፡ ይመጣሉ ÷ በእግዚአብሔርም ፡ መንግሥት ፡ ፴ በማዕድ ፡ ይቀመጣሉ ። እነሆም ÷ ከኋለኞች ፡ ፊተኞች ፡ የሚሆኑ ፡ አሉ ÷ ከፊተኞችም ፡ ኋለ ኞች ፡ የሚሆኑ ፡ አሉ ።

፴፩ በዚያን ፡ ሰዓት ፡ ከፈሪሳውያን ፡ አንዳንዱ ፡ ቀርበው ፡— ሄሮድስ ፡ ሊገድልህ ፡ ይወዳልና ፡ ፴፪ ከዚህ ፡ ውጣና ፡ ሂድ ፡ አሉት ። እንዲህም ፡ አላቸው ፡— ሂዳችሁ ፡ ለዚያች ፡ ቀበሮ ፡— እነሆ ÷ ዛሬና ፡ ነገ ፡ አጋንንትን ፡ አወጣለሁ ፡ በሽተኞች ንም ፡ እፈውሳለሁ ÷ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ እፈጸ ፴፫ ማለሁ ፡ በሉአት ። ዳሩ ፡ ግን ፡ ነቢይ ፡ ከኢየሩሳ ሌም ፡ ውጭ ፡ ይጠፋ ፡ ዘንድ ፡ አይገባምና ፡ ዛሬና ፡ ነገ ፡ ከነገ ፡ በስቲያም ፡ ልሄድ ፡ ያስፈልገኛል ። ፴፬ ኢየሩሳሌም ÷ ኢየሩሳሌም ÷ ነቢያትን ፡ የምትገ ድል ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ የተላኩትንም ፡ የምትወ ግር ÷ ዶሮ ፡ ጫጩቶችዋን ፡ በክንፎችዋ ፡ በታች ፡ እንደምትሰበስብ ፡ ልጆችሽን ፡ ልሰበስብ ፡ ዘንድ ፡ ስንት ፡ ጊዜ ፡ ወደድሁ ÷ እናንተም ፡ አልወደዳ ፴፭ ችሁም ። እነሆ ÷ ቤታችሁ ፡ የተፈታ ፡ ሆኖ ፡ ይቀ ርላችኋል ። እላችኋለሁም ÷ በጌታ ፡ ስም ፡ የሚ መጣ ፡ የተባረከ ፡ ነው ፡ እስክትሉ ፡ ድረስ ፡ ከእ ንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አታዩኝም ።

ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ በሰንበትም ፡ ከፈሪሳውያን ፡ አለቆች ፡ ወደ ፡ አንዱ ፡ ቤት ፡ እንጀራ ፡ ሊበላ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ እነ ፪ ርሱ ፡ ይጠባበቁት ፡ ነበር ። እነሆም ÷ ሆዱ ፡ ፫ የተነፋ ፡ ሰው ፡ በፊቱ ፡ ነበረ ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡— በሰንበት ፡ መፈወስ ፡ ተፈቅዶአልን ፡ ወይስ ፡ አልተፈቀደም ? ብሎ ፡ ለሕግ ፡ አዋቂ ፬ ዎችና ፡ ለፈሪሳውያን ፡ ተናገረ ። እነርሱ ፡ ግን ፡ ዝም ፡ አሉ ። ይዞም ፡ ፈወሰውና ፡ አሰናበተው ። ፭ ከእናንተ ፡ አህያው ፡ ወይስ ፡ በሬው ፡ በጕድጓድ ፡ ቢወድቅ ፡ በሰንበት ፡ ወዲያው ፡ የማያወጣው ፡ ፮ ማን ፡ ነው ? አላቸው ። ስለዚህ ፡ ነገርም ፡ ሊመ ልሱለት ፡ አልተቻላቸውም ።

፯ የታደሙትንም ፡ የከበሬታ ፡ ስፍራ ፡ እንደ ፡ መረጡ ፡ ተመልክቶ ፡ ምሳሌ ፡ ነገራቸው ፡ እን ፰ ዲህ ፡ ሲል ፡— ማንም ፡ ለሰርግ ፡ ቢጠራህ ፡ በከ በሬታ ፡ ስፍራ ፡ አትቀመጥ ፤ ምናልባት ፡ ከአ ንተ ፡ ይልቅ ፡ የከበረ ፡ ተጠርቶ ፡ ይሆናልና ፡ ፱ አንተን ፡ እርሱንም ፡ የጠራ ፡ መጥቶ ፡— ለዚህ ፡ ስፍራ ፡ ተውለት ፡ ይልሃል ÷ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ እያፈርህ ፡ በዝቅተኛው ፡ ስፍራ ፡ ልትሆን ፡ ትጀ ፲ ምራለህ ። ነገር ፡ ግን ፡ በተጠራህ ፡ ጊዜ ÷ የጠ ራህ ፡ መጥቶ ፡— ወዳጄ ፡ ሆይ ÷ ወደ ፡ ላይ ፡ ውጣ ፡ እንዲልህ ÷ ሄደህ ፡ በዝቅተኛው ፡ ስፍራ ፡ ተቀመጥ ፤ ያን ፡ ጊዜም ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ በተ ቀመጡት ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ክብር ፡ ይሆንልሃል ። ፲፩ ራሱን ፡ ከፍ ፡ የሚያደርግ ፡ ሁሉ ፡ ይዋረዳልና ÷ ራሱንም ፡ የሚያዋርድ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።

፲፪ የጠራውንም ፡ ደግሞ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— ምሳ ፡ ወይም ፡ እራት ፡ ባደረግህ ፡ ጊዜ ÷ እነርሱ ፡ ደግሞ ፡ በተራቸው ፡ ምናልባት ፡ እንዳይጠሩህ ፡ ብድራትም ፡ እንዳይመልሱልህ ÷ ወዳጆችህንና ፡ ወንድሞችህን ፡ ዘመዶችህንም ፡ ባለ ፡ ጠጎች ፡ ጎረ ፲፫ ቤቶችህንም ፡ አትጥራ ። ነገር ፡ ግን ፡ ግብዣ ፡ ባደረግህ ፡ ጊዜ ፡ ድሆችንና ፡ ጕንድሾችን ፡ አን ፲፬ ካሶችንም ፡ ዕውሮችንም ፡ ጥራ ፤ የሚመልሱት ፡ ብድራት ፡ የላቸውምና ፡ ብፁዕ ፡ ትሆናለህ ፤ በጻ ድቃን ፡ ትንሣኤ ፡ ይመለስልሃልና ።

፲፭ ከተቀመጡትም ፡ አንዱ ፡ ይህን ፡ ሰምቶ ፡— በእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ እንጀራ ፡ የሚ ፲፮ በላ ፡ ብፁዕ ፡ ነው ፡ አለው ። እርሱ ፡ ግን ፡ እን ዲህ ፡ አለው ፡— አንድ ፡ ሰው ፡ ታላቅ ፡ እራት ፡ ፲፯ አድርጎ ፡ ብዙዎችን ፡ ጠራ ፤ በእራትም ፡ ሰዓት ፡ የታደሙትን ፡— አሁን ፡ ተዘጋጅቶአልና ፡ ኑ ፡ ፲፰ እንዲላቸው ፡ ባሪያውን ፡ ላከ ። ሁላቸውም ፡ በአንድነት ፡ ያመካኙ ፡ጀመር ። የፊተኛው ፡— መሬት ፡ ገዝቼአለሁ ፡ ወጥቼም ፡ ላየው ፡ በግድ ፡ ያስፈልገኛል ፤ ይቅር ፡ እንድትለኝ ፡ እለምንሃ ፲፱ ለሁ ፡ አለው ። ሌላውም ፡— አምስት ፡ ጥምድ ፡ በሬዎች ፡ ገዝቼአለሁ ፡ ልፈትናቸውም ፡ እሄዳ ለሁ ፤ ይቅር ፡ እንድትለኝ ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለው ። ፳ ሌላውም ፡— ሚስት ፡ አግብቼአለሁ ፡ ስለዚህም ፡ ፳፩ ልመጣ ፡ አልችልም ፡ አለው ። ባሪያውም ፡ ደርሶ ፡ ይህን ፡ ለጌታው ፡ ነገረው ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ባለቤቱ ፡ ተቆጥቶ ፡ ባሪያውን ፡— ወደ ፡

፲፫ ። ፳፫ ፡ ፳፬ ፤ ማቴ. ፯ ÷ ፲፫ ፡ ፲፬ ። ፳፭—፳፯ ፤ ማቴ. ፯ ÷ ፳፪ ፡ ፳፫ ፡ ፳፭ ÷ ፲—፲፪ ። ፳፯ ፤ መዝ. ፮ ÷ ፰ ። ፳፰ ፡ ፳፱ ፡ ማቴ. ፰ ÷ ፲፩ ፡ ፲፪ ። ፴ ፤ ኢሳ. ፶፱ ÷ ፲፱ ፡ ፳ ። ፴ ፤ ማቴ. ፲፱ ÷ ፴ ። ፴፬ ፡ ፴፭ ፡ ማቴ. ፳፫ ÷ ፴፯—፴፱ ። ፴፭ ፡ መዝ. ፳፰ ÷ ፳፭ ፤ ፲፯፯ ÷ ፳፮ ፤ ሚል. ፫ ÷ ፲፱ ።

፲፬ ። ፩—፮ ፤ ምሳ. ፯ ÷ ፮—፲ ። ፭ ፤ ምሳ. ፲፫ ÷ ፲፭ ። ፰ ፤ ማቴ. ፳፫ ÷ ፮ ። ፲፩ ፤ ማቴ. ፳፫ ÷ ፲፪ ። ፲፮—፳፬ ፤ ማቴ. ፳፪ ÷ ፪—፲ ።

ከተማ፡ ጎዳናና፡ ወደ፡ ስላች፡ ፈጥነህ፡ ውጣ፡
ድሆችንና፡ ጕንድሾችን፡ እንከሶችንና፡ ዕውሮች
፳፪ ንም፡ ወደዚህ፡ አግባ፡ አለው። ባሪያውም፡—
ጌታ፡ ሆይ፥ እንዳዘዝኸኝ፡ ተደርጎአል፥ ገናም፡
፳፫ ስፍራ፡ አለ፡ አለው። ጌታውም፡ ባሪያውን፡—
ቤቴ፡ እንዲሞላ፡ ወደ፡ መንገድና፡ ወደ፡ ቅጥር፡
፳፬ ውጣና፡ ይግቡ፡ ዘንድ፡ ግድ፡ በላቸው፤ እላች
ኋለሁና፥ ከታደሙቱ፡ ከእነዚያ፡ ሰዎች፡ አንድ፡
ስንኳ፡ እራቴን፡ አይቀምስም፡ አለው።

፳፭ ብዙም፡ ሕዝብ፡ ከእርሱ፡ ጋር፡ ይሄዱ፡ ነበር፥
፳፮ ዘወር፡ ብሎም፡ እንዲህ፡ አላቸው፡— ማንም፡
ወደ፡ እኔ፡ የሚመጣ፡ ቢኖር፡ አባቱንና፡ እና
ቱን፡ ሚስቱንም፡ ልጆቹንም፡ ወንድሞቹንም፡
እኅቶቹንም፡ የራሱን፡ ሕይወት፡ ስንኳ፡ ሳይ
ቀር፡ ባይጠላ፥ ደቀ፡ መዝሙሬ፡ ሊሆን፡ አይ
፳፯ ችልም። ማንም፡ መስቀሉን፡ ተሸክሞ፡ በኋ
ላዬ፡ የማይመጣ፥ ደቀ፡ መዝሙሬ፡ ሊሆን፡
፳፰ አይችልም። ከእናንተ፡ ግንብ፡ ሊሠራ፡ የሚ
ወድ፡ ስለመደምደሚያ፡ የሚበቃ፡ ያለው፡ እንደ፡
ሆነ፡ አስቀድሞ፡ ተቀምጦ፡ ከሳራውን፡ የማ
፳፱ ይቈጥር፡ ማን፡ ነው? ያለዚያ፡ መሠረቱን፡
ቢመሠርት፥ ሊደመድመውም፡ ቢያቅተው፥
፴ ያዩት፡ ሁሉ፡— ይህ፡ ሰው፡ ሊሠራ፡ ጀምሮ፡
ሊደመድመው፡ አቃተው፡ ብለው፡ ሊዘብቱ
፴፩ በት፡ ይጀምራሉ። ወይም፡ ሌላውን፡ ንጉሥ፡
በጦርነት፡ ሊጋጠም፡ የሚሄድ፥ ከሁለት፡ እልፍ፡
ጋር፡ የሚመጣበትን፡ በአንድ፡ እልፍ፡ ሊገናኝ፡
የሚችል፡ እንደ፡ ሆነ፡ አስቀድሞ፡ ተቀምጦ፡
፴፪ የማያስብ፡ ንጉሥ፡ ማን፡ ነው? ባይሆንስ፡
ሌላው፡ ገና፡ ሩቅ፡ ሳለ፡ መልክተኞች፡ ልኮ፡
፴፫ ዕርቅ፡ ይለምናል። እንግዲህ፡ እንደዚሁ፡
ማንም፡ ከእናንተ፡ ያለውን፡ ሁሉ፡ የማይተው፡
ደቀ፡ መዝሙሬ፡ ሊሆን፡ አይችልም።

፴፬ ጨው፡ መልካም፡ ነው፤ ጨው፡ አልጫ፡
፴፭ ቢሆን፡ ግን፡ በምን፡ ይጣፈጣል? ለምድር፡
ቢሆን፡ ለፍግ፡ መቈለያም፡ ቢሆን፡ አይረባም፤
ወደ፡ ውጭ፡ ይጥሉታል። የሚሰማ፡ ጆሮ፡
ያለው፡ ይስማ።

ምዕራፍ፡ ፲፭።

፩ ተራጮችና፡ ኃጢአተኞችም፡ ሁሉ፡ ሊሰ
፪ ሙት፡ ወደ፡ እርሱ፡ ይቀርቡ፡ ነበር። ፈሪሳው
ያንና፡ ሳፎችም፡— ይህስ፡ ኃጢአተኞችን፡ ይቀ
በላል፡ ከእነርሱም፡ ጋር፡ ይበላል፡ ብለው፡ እርስ፡
በርሳቸው፡ አንጐራጐሩ።

፫ ይህንም፡ ምሳሌ፡ ነገራቸው፡ እንዲህ፡ ሲል፡—
፬ መቶ፡ በግ፡ ያለው፡ ከእነርሱም፡ አንዱ፡ ቢጠፋ፥
ዘጠና፡ ዘጠኙን፡ በበረሃ፡ ትቶ፡ የጠፋውን፡
አስኪያገኘው፡ ድረስ፡ ሊፈልገው፡ የማይሄድ፡
፭ ከእናንተ፡ ማን፡ ነው? ባገኘውም፡ ጊዜ፡ ደስ፡
፮ ብሎት፡ በጫንቃው፡ ይሸከመዋል፤ ወደ፡
ቤትም፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ወዳጆቹንና፡ ጐረቤቶ
ቹን፡ በአንድነት፡ ጠርቶ፡— የጠፋውን፡ በጌን፡
አግኝቼዋለሁና፡ ከእኔ፡ ጋር፡ ደስ፡ ይበላችሁ፡
፯ ይላቸዋል። እላችኋለሁ፥ እንዲሁ፡ ንስሓ፡
ከማያስፈልጋቸው፡ ከዘጠና፡ ዘጠኝ፡ ጻድቃን፡
ይልቅ፡ ንስሐ፡ በሚገባ፡ በአንድ፡ ኃጢአተኛ፡
በሰማይ፡ ደስታ፡ ይሆናል።

፰ ወይም፡ አሥር፡ ድሪም፡ ያላት፡ አንድ፡ ድሪም፡
ቢጠፋባት፥ መብራት፡ አብርታ፡ ቤትዋንም፡
ጠርጋ፡ አስከታገኘው፡ ድረስ፡ አጥብቃ፡ የማ
፱ ትፈልግ፡ ሴት፡ ማን፡ ናት? ባገኘችውም፡ ጊዜ፡
ወዳጆችዋንና፡ ጐረቤቶችዋን፡ በአንድነት፡
ጠርታ፡— የጠፋውን፡ ድሪሜን፡ አግኝቼዋለ
ሁና፡ ከእኔ፡ ጋር፡ ደስ፡ ይበላችሁ፡ ትላቸዋለች።
፲ እላችኋለሁ፥ እንዲሁ፡ ንስሐ፡ በሚገባ፡ በአንድ፡
ኃጢአተኛ፡ በእግዚአብሔር፡ መላእክት፡ ፊት፡
ደስታ፡ ይሆናል።

፲፩ እንዲህም፡ አለ፡— አንድ፡ ሰው፡ ሁለት፡
፲፪ ልጆች፡ ነበሩት። ከእነርሱም፡ ታናሹ፡ አባ
ቱን፡— አባቴ፡ ሆይ፥ ከገንዘብህ፡ የሚደርሰኝን፡
ክፍል፡ ስጠኝ፡ አለው። ገንዘቡንም፡ አካፈላ
፲፫ ቸው። ከጥቂት፡ ቀንም፡ በኋላ፡ ታናሹ፡ ልጅ፡
ገንዘቡን፡ ሁሉ፡ ሰብስቦ፡ ወደ፡ ሩቅ፡ አገር፡ ሄደ፥
፲፬ ከዚያም፡ እያባከነ፡ ገንዘቡን፡ በተነ። ሁሉ
ንም፡ ከከሰረ፡ በኋላ፡ በዚያች፡ አገር፡ ጽኑ፡ ራብ፡
፲፭ ሆነ፥ እርሱም፡ ይጨነቅ፡ ጀመር። ሄዶም፡
ከዚያች፡ አገር፡ ሰዎች፡ ከአንዱ፡ ጋር፡ ተዳበለ፥
እርሱም፡ እሪያ፡ ሊያሰማራ፡ ወደ፡ ሜዳ፡ ሰደ
፲፮ ደው። እሪያዎችም፡ ከሚበሉት፡ አሰር፡ ሊጠ
ግብ፡ ይመኝ፡ ነበር፥ የሚሰጠውም፡ አልነበረም።
፲፯ ወደ፡ ልቡም፡ ተመልሶ፡ እንዲህ፡ አለ፡— እን
ጀራ፡ የሚተርፋቸው፡ የአባቴ፡ ሞያተኞች፡
ስንት፡ ናቸው? እኔ፡ ግን፡ ከዚህ፡ በራብ፡ እጠፋ
፲፰ ለሁ። ተነሥቼም፡ ወደ፡ አባቴ፡ እሄዳለሁና፡—
አባቴ፡ ሆይ፥ በሰማይና፡ በፊትህ፡ በደልሁ፥
፲፱ ወደ፡ ፊትም፡ ልጅህ፡ ልባል፡ አይገባኝም፤
ከሞያተኞችህ፡ እንደ፡ አንዱ፡ አድርገኝ፡ እለዋ
፳ ለሁ። ተነሥቶም፡ ወደ፡ አባቱ፡ መጣ። እር
ሱም፡ ገና፡ ሩቅ፡ ሳለ፡ አባቱ፡ አየውና፡ አዘነ
ለት፥ሮጦም፡ አንገቱን፡ አቀፈውና፡ ሳመው።
፳፩ ልጁም፡— አባቴ፡ ሆይ፥ በሰማይና፡ በፊትህ፡
በደልሁ፥ ወደ፡ ፊትም፡ ልጅህ፡ ልባል፡ አይገ
፳፪ ባኝም፡ አለው። አባቱ፡ ግን፡ ባሪያዎቹን፡
አለ፡— ፈጥናችሁ፡ ከሁሉ፡ የተሻለ፡ ልብስ፡
አምጡና፡ አልብሱት፥ ለእጁ፡ ቀለበት፡ ለእግ
፳፫ ሩም፡ ጫማ፡ ስጡ፤ የሰባውን፡ ፊሪዳ፡ አምጥ
ታችሁ፡ እረዱት፥ እንብላም፡ ደስም፡ ይበለን፤
፳፬ ይህ፡ ልጄ፡ ሞቶ፡ ነበርና፡ ደግሞም፡ ሕያው፡
ሆኖአል፤ ጠፍቶም፡ ነበር፡ ተገኝቶአልም።
ደስም፡ ይላቸው፡ ጀመር።

፳፭ ታላቁ፡ ልጁ፡ በእርሻ፡ ነበረ፤ መጥቶም፡

፲፬። ፳፮፤ ማቴ፡ ፲፥፴፯። ፳፯፤ ምዕ፡ ፱፥፳፫፤ ማቴ፡ ፲፥፴፰፤ ፲፮፥፳፬። ፴፬፤ ማቴ፡ ፭፥፲፫፤ ማር፡ ፱፥፶። [illegible]
፲፭። [illegible]

ወደ ፡ ቤት ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፡ የመሰንቆና ፡ የዘ
፳፮ ፈን ፡ ድምፅ ፡ ሰማ ፤ ከብላቴናዎችም ፡ አንዱን ፡
ጠርቶ ፡— ይህ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብሎ ፡ ጠየቀ ።
፳፯ እርሱም ፡— ወንድምህ ፡ መጥቶአልና ፡ በደኅና ፡
ስላገኘው ፡ አባትህ ፡ የሰባውን ፡ ፊሪዳ ፡ አረደለት ፡
፳፰ አለው ። ተቈጣም ፡ ሊገባም ፡ አልወደደም ፤
፳፱ አባቱም ፡ ወጥቶ ፡ ለመነው ። እርሱ ፡ ግን ፡ መልሶ ፡
አባቱን ፡— እነሆ ፥ ይህን ፡ ያህል ፡ ዓመት ፡ እንደ ፡
ባሪያ ፡ ተገዝቼልሃለሁ ፥ ከትእዛዝህም ፡ ከቶ ፡
አልተላለፍሁም ፤ ለእኔም ፡ ከወዳጆቼ ፡ ጋር ፡
ደስ ፡ እንዲለኝ ፡ አንድ ፡ ጥቦት ፡ ስንኳ ፡ አልሰጠ
፴ ኸኝም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ገንዘብህን ፡ ከጋለሞቶች ፡
ጋር ፡ በልቶ ፡ ይህ ፡ ልጅህ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፥ የሰ
፴፩ ባውን ፡ ፊሪዳ ፡ አረድህለት ፡ አለው ። እርሱ ፡
ግን ፡— ልጄ ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ሁልጊዜ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡
፴፪ ነህ ፥ ለእኔም ፡ የሆነ ፡ ሁሉ ፡ የአንተ ፡ ነው ፤ ዳሩ ፡
ግን ፡ ይህ ፡ ወንድምህ ፡ ሞቶ ፡ ነበረ ፡ሕያው ፡
ስለ ፡ ሆነ ፡ ጠፍቶም ፡ ነበር ፡ ስለ ፡ ተገኘ ፡ ደስ ፡
እንዲለን ፡ ፍሥሐም ፡ እንድናደርግ ፡ ይገባናል ፡
አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ ደግሞም ፡ ለደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ እንዲህ ፡
አለ ፡— መጋቢ ፡ የነበረው ፡ አንድ ፡ ባለ ፡ ጠጋ ፡
ሰው ፡ ነበረ ፥ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡— ይህ ፡ ሰው ፡
፪ ያለህን ፡ ይበትናል ፡ ብለው ፡ ከሰሱት ። ጠር
ቶም ፡— ይህ ፡ የምሰማብህ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
ወደ ፡ ፊት ፡ ለእኔ ፡ መጋቢ ፡ ልትሆን ፡ አትች
ልምና ፡ የመጋቢነትህን ፡ ሒሳብ ፡ አስረክበኝ ፡
፫ አለው ። መጋቢውም ፡ በልቡ ፡— ጌታዬ ፡ መጋ
ቢነቱን ፡ ከእኔ ፡ ይወስዳልና ፡ ምን ፡ ላድርግ ?
ለመቈፈር ፡ ኃይል ፡ የለኝም ፥ መለመንም ፡ አፍ
፬ ራለሁ ። ከመጋቢነቱ ፡ብሻር ፡ በቤታቸው ፡ እን
ዲቀበሉኝ ፡ የማደርገውን ፡ አውቃለሁ ፡ አለ ።
፭ የጌታውንም ፡ ባለ ፡ ዕዳዎች ፡ እያንዳንዳቸው ፡
ጠርቶ ፡ የፊተኛውን ፡— ለጌታዬ ፡ ምን ፡ ያህል ፡
፮ ዕዳ ፡ አለብህ ? አለው ። እርሱም ፡— መቶ ፡
ማድጋ ፡ ዘይት ፡ አለ ። ደብዳቤህን ፡ እንካ ፡ ፈጥ
ነህም ፡ ተቀምጠህ ፡ አምሳ ፡ ብለህ ፡ጻፍ ፡ አለው ።
፯ በኋላም ፡ ሌላውን ፡— አንተስ ፡ ስንት ፡ ዕዳ ፡
አለብህ ? አለው ። እርሱም ፡— መቶ ፡ ሰፍሮ ፡
ስንዴ ፡ አለ ። ደብዳቤህን ፡ እንካ ፡ ሰማንያ ፡ ብለ
፰ ህም ፡ ጻፍ ፡ አለው ። ጌታውም ፡ዓመፀኛውን ፡
መጋቢ ፡ በልባምነት ፡ ስላደረገ ፡ አመሰገነው ፤
የዚህ ፡ ዓለም ፡ ልጆች ፡ ለትውልዳቸው ፡ ከብ
ርሃን ፡ ልጆች ፡ ይልቅ ፡ ልባሞች ፡ ናቸውና ።
፱ እኔም ፡ እላችኋለሁ ፥ የዓመፃ ፡ ገንዘብ ፡ ሲያልቅ ፡
በዘላለም ፡ ቤቶች ፡ እንዲቀበሉአችሁ ፥ በእርሱ ፡
ወዳጆችን ፡ ለራሳችሁ ፡ አድርጉ ።
፲ ከሁሉ ፡ በሚያንስ ፡ የታመነ ፡ በብዙ ፡ ደግሞ ፡
የታመነ ፡ ነው ፥ ከሁሉ ፡ በሚያንስም ፡ የሚያ
፲፩ ምፅ ፡ በብዙ ፡ ደግሞ ፡ ዓመፀኛ ፡ ነው ። እንግዲ
ያስ ፡ በዓመፃ ፡ ገንዘብ ፡ ካልታመናችሁ ፥ እውነ
ተኛውን ፡ ገንዘብ ፡ ማን ፡ አደራ ፡ ይሰጣችኋል ?
፲፪ በሌላ ፡ ሰው ፡ ገንዘብም ፡ ካልታመናችሁ ፥ የእ
፲፫ ናንተን ፡ ማን ፡ ይሰጣችኋል ? ለሁለት ፡ ጌቶች ፡
መገዛት ፡ የሚቻለው ፡ ባሪያ ፡ማንም ፡ የለም ፤
ወይም ፡ አንዱን ፡ ይጠላልና ፡ ሁለተኛውንም ፡
ይወዳል ፥ ወይም ፡ ወደ ፡ አንዱ ፡ ይጠጋል ፡ ሁለ
ተኛውንም ፡ ይንቃል ። ለእግዚአብሔርና ፡
ለገንዘብ ፡ መገዛት ፡ አትችሉም ።
፲፬ ገንዘብንም ፡ የሚወዱ ፡ ፈሪሳውያን ፡ ይህን ፡
፲፭ ሁሉ ፡ ሰምተው ፡ ያፌዙበት ፡ ነበር ። እንዲ
ህም ፡ አላቸው ፡— ራሳችሁን ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ የም
ታጸድቁ ፡ እናንተ ፡ ናችሁ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ልባችሁን ፡ ያውቃል ፤ በሰው ፡ ዘንድ ፡
የከበረ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ርኵሰት ፡ ነውና ።
፲፮ ሕግና ፡ ነቢያት ፡ እስከ ፡ ዮሐንስ ፡ ነበሩ ፤ ከዚያ ፡
ጀምሮ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ይሰበ
ካል ፤ ሁሉም ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ በኃይል ፡ ይገቡ
፲፯ ባታል ። ነገር ፡ ግን ፡ ከሕግ ፡ አንዲት ፡ ነጥብ ፡
ከምትወድቅ ፡ሰማይና ፡ ምድር ፡ ሊያልፍ ፡ ይቀ
ላል ።
፲፰ ሚስቱንም ፡ የሚፈታ ፡ ሁሉ ፡ ሌላይቱንም ፡
የሚያገባ ፡ ያመነዝራል ፥ ከባልዋም ፡ የተፈታ
ችውን ፡ የሚያገባ ፡ ያመነዝራል ።
፲፱ ቀይ ፡ ልብስና ፡ቀጭን ፡ የተልባ ፡ እግር ፡ የለ
በሰ ፡ አንድ ፡ ባለ ፡ ጠጋ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፥ ዕለት ፡
ዕለትም ፡ እየተመቻቸ ፡ በደስታ ፡ ይኖር ፡ ነበር ።
፳ አልዓዛርም ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ድሀ ፡ በቍስል ፡
፳፩ ተወርሶ ፡ በደጁ ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ፥ ከባለ ፡ ጠጋ
ውም ፡ ማዕድ ፡ ከሚወድቀው ፡ ፍርፋሪ ፡ ሊጠ
ግብ ፡ ይመኝ ፡ ነበር ፤ ውሾች ፡ አንኳ ፡ መጥተው ፡
፳፪ ቍስሎቹን ፡ ይልሱ ፡ ነበር ። ድሀውም ፡ ሞተ ፥
መላእክትም ፡ ወደ ፡ አብርሃም ፡ እቅፍ ፡ ወሰ
ዱት ፤ ባለ ፡ ጠጋው ፡ ደግሞ ፡ ሞተና ፡ ተቀበረ ።
፳፫ በሲኦልም ፡ በሥቃይ ፡ሳለ ፡ አሻቅቦ ፡ አብርሃ
ምን ፡ በሩቅ ፡ አየ ፡ አልዓዛርንም ፡ በእቅፉ ።
፳፬ እርሱም ፡ እየጮኸ ፡— አብርሃም ፡ አባት ፡ ሆይ ፥
ማረኝ ፥ በዚህ ፡ ነበልባል ፡ እሣቀያለሁና ፡ የጣ
ቱን ፡ ጫፍ ፡ በውኃ ፡ ነክሮ ፡ መላሴን ፡ እንዲያ
በርድልኝ ፡ አልዓዛርን ፡ ስደድልኝ ፡ አለ ። አብ
፳፭ ርሃም ፡ ግን ፡— ልጄ ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ በሕይወ
ትህ ፡ሳለህ ፡ መልካም ፡ እንደ ፡ ተቀበልህ ፡ አስብ ፡
አልዓዛርም ፡ እንዲሁ ፡ ክፉ ፤ አሁን ፡ ግን ፡ እርሱ ፡
፳፮ በዚህ ፡ ይጽናናል ፡ አንተም ፡ ትሣቀያለህ ። ከዚ
ህም ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ከዚህ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ሊያ
ልፉ ፡ የሚፈልጉ ፡ እንዳይችሉ ፥ ወዲያ ፡ ያሉ ፡
ደግሞ ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ እንዳይሻገሩ ፡ በእኛና ፡ በእና
ንተ ፡ መካከል ፡ታላቅ ፡ገደል ፡ ተደርጎአል ፡ አለ ።
፳፯ እርሱም ፡— እንኪያስ ፥ አባት ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡
አባቴ ፡ ቤት ፡ እንድትሰደው ፡ እለምንሃለሁ ፤
፳፰ አምስት ፡ ወንድሞች ፡ አሉኝና ፤ እነርሱ ፡ ደግሞ ፡
ወደዚህ ፡ ሥቃይ ፡ ስፍራ ፡ እንዳይመጡ ፡ ይመስ

፲፮ ። ፩ ፡ የሐ ፲፪ ፡ ፴፯ ። ፱ ፡ ማቴ ፲፱ ፡ ፳፩ ። ፲ ፡ ም ፲፱ ፡ ፲፯ ። ፲፫ ፡ ማቴ ፮ ፡ ፳፬ ። ፲፮ ፡ ም ፲፯ ፡ ፱ ።
፲፮ ፡ ማቴ ፲፩ ፡ ፲፪ ፡ ፲፫ ። ፲፯ ፡ ማቴ ፭ ፡ ፲፰ ። ፲፰ ፡ ማቴ ፭ ፡ ፴፪ ።

፳፱ ከርሳቸው ፡ አለ ። አብርሃም ፡ ግን ፡— ሙሴና ፡ ነቢያት ፡ አሉአቸው ፤ እነርሱን ፡ ይስሙ ፡ አለው ። ፴ እርሱም ፡— አይደለም ፥ አብርሃም ፡ አባት ፡ ሆይ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ከሙታን ፡ አንዱ ፡ ቢሄድላቸው ፡ ፴፩ ንስሐ ፡ ይገቡሉ ፡ አለ ። ሙሴንና ፡ ነቢያትንም ፡ የማይሰሙ ፡ ከሆነ ፥ ከሙታንም ፡ እንኳ ፡ አንድ ፡ ቢነሣ ፡ አያምኑም ፡ አለው ።

ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ ለደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— መሰናከል ፡ግድ ፡ ሳይመጣ ፡ አይቀርም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ፪ መሰናክሉን ፡ ለሚያመጣው ፡ ወዮለት ፤ ከእነ ዚህ ፡ ከታናናሾች ፡ አንዱን ፡ ከማሰናከል ፡ይልቅ ፡ የወፍጮ ፡ ድንጋይ ፡ በአንገቱ ፡ ታስሮ ፡ ወደ ፡ ፫ ባሕር ፡ ቢጣል ፡ ይጠቅመው ፡ ነበር ። ለራሳችሁ ፡ ተጠንቀቁ ። ወንድምህ ፡ ቢበድልህ ፡ ገሥጸው ፥ ፬ ቢጸጸትም ፡ ይቅር ፡ በለው ። በቀንም ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡ እንኳ ፡ ቢበድልህ ፡ በቀንም ፡ ሰባት ፡ ጊዜ ፡— ተጸጸትሁ ፡ እያለ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ቢመለስ ፥ ይቅር ፡ በለው ።

፭ ሐዋርያትም ፡ ጌታን ፡— እምነት ፡ ጨምርልን ፡ ፮ አሉት ። ጌታም ፡ አለ ፡— የሰናፍጭ ፡ ቅንጣት ፡ የሚያህል ፡ እምነት ፡ ቢኖራችሁ ፥ ይህን ፡ሾላ ፡— ተነቅለህ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ተተከል ፡ ብትሉት ፥ ይታዘዝላችሁ ፡ ነበር ።

፯ ከእናንተም ፡ የሚያርስ ፡ ወይም ፡ ከብትን ፡ የሚጠብቅ ፡ባሪያ ፡ ያለው ፥ ከእርሻ ፡ሲመለስ ፡— ወዲያው ፡ ቀረብና ፡ በማዕድ ፡ ተቀመጥ ፡ የሚ ፰ ለው ፡ማን ፡ነው ? የምበላውን ፡ አሰናዳልኝ ፥ እስክበላና ፡ እስክጠጣ ፡ ድረስ ፡ ታጥቀህ ፡ አገልግለኝ ፥ በኋላም ፡ አንተ ፡ ብላና ፡ ጠጣ ፡ የሚ ፱ ለው ፡ አይደለምን ? ያንን ፡ ባሪያ ፡ ያዘዘውን ፡ ፲ ስላደረገ ፡ ያመሰግነዋልን ? እንዲሁ ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ የታዘዛችሁትን ፡ ሁሉ ፡ በደረጋችሁ ፡ ጊዜ ፡— የማንጠቅም ፡ ባሪያዎች ፡ ነን ፥ ልናደ ርገው ፡ የሚገባንን ፡ አድርገናል ፡ በሉ ።

፲፩ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ሲሄድ ፡ በገሊላና ፡ በሰ ፲፪ ማርያ ፡ መካከል ፡ አለፈ ። ወደ ፡ አንዲት ፡ መን ደርም ፡ ሲገባ ፡ በሩቅ ፡ የቆሙት ፡ አሥር ፡ ለም ፲፫ ጻሞች ፡ ተገናኙት ፤ እነርሱም ፡ እየጮኹ ፡— ፲፬ ኢየሱስ ፡ ሆይ ፥ አቤቱ ፥ ማረን ፡ አሉ ። አይ ቶም ፡— ሂዱ ፥ ራሳችሁን ፡ ለካህናት ፡ አሳዩ ፡ አላ ፲፭ ቸው ። እነሆም ፥ ቢሄዱ ፡ ነጹ ። ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ እንደ ፡ ተፈወሰ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እያከበረ ፡ ተመለሰ ፥ ፲፮ እያመሰገነውም ፡ በእግሩ ፡ ፊት ፡ በግንባሩ ፡ ፲፯ ወደቀ ፤ እርሱም ፡ ሳምራዊ ፡ነበረ ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡— አሥሩ ፡ አልነጹምን ? ዘጠኙስ ፡ ፲፰ ወዴት ፡ አሉ ? ከዚህ ፡ ከልዩ ፡ ወገን ፡ በቀር ፡ እግዚአብሔርን ፡ ሊያከብሩ ፡ የተመለሱ ፡ አል ፲፱ ተገኙም ፡ አለ ። እርሱንም ፡— ተነሣና ፡ ሂድ ፤ እምነትህ ፡ አድኖሃል ፡ አለው ።

፳ ፈሪሳውያንም ፡— የእግዚአብሔር ፡ መንግ ሥት ፡ መቼ ፡ ትመጣለች ፡ ብለው ፡ ቢጠይቁት ፥ መልሶ ፡— የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ በመ ፳፩ ጠባበቅ ፡ አትመጣም ፤ ደግሞም ፡— እንኋት ፡ በዚህ ፡ ወይም ፡— እንኋት ፡ በዚያ ፡ አይሉአ ትም ። እነሆ ፥ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ በመካከላችሁ ፡ ናትና ፡ አላቸው ።

፳፪ ለደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ከሰው ፡ ልጅ ፡ ቀናች ፡ አንዱን ፡ ልታዩ ፡ የምት መኙበት ፡ ወራት ፡ ይመጣል ፡ አታዩትምም ። ፳፫ እነርሱም ፡— እነሆ ፡ በዚህ ፥ ወይም ፡— እነሆ ፡ በዚያ ፡ ይሉአችኋል ፤ አትሂዱ ፡ አትከተሉአ ፳፬ ቸውም ። መብረቅ ፡ በርቆ ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡ ካለ ፡ ከአንድ ፡ አገር ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡ወዳለው ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ አገር ፡ እንደሚያበራ ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ ፳፭ በቀኑ ፡ እንዲሁ ፡ ይሆናል ። አስቀድሞ ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ መከራ ፡ እንዲቀበል ፡ ከዚህም ፡ ትውልድ ፡ ፳፮ እንዲጣል ፡ ይገባዋል ። በኖኅ ፡ ዘመንም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ በሰው ፡ ልጅ ፡ ዘመን ፡ ደግሞ ፡ እንዲሁ ፡ ፳፯ ይሆናል ። ኖኅ ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ እስከ ፡ ገባበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፥ ይበሉና ፡ ይጠጡ ፡ ያገቡና ፡ ይጋ ቡም ፡ ነበር ፥ የጥፋት ፡ ውኃም ፡ መጣ ፡ ሁሉንም ፡ ፳፰ አጠፋ ። እንዲሁ ፡ በሎጥ ፡ ዘመን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፤ ይበሉ ፡ ይጠጡም ፡ ይገዙም ፡ ይሸጡም ፡ ይተ ፳፱ ክሉም ፡ ቤትም ፡ ይሠሩ ፡ ነበር ፤ ሎጥ ፡ ከሰዶም ፡ በወጣበት ፡ ቀን ፡ ግን ፡ ከሰማይ ፡ እሳትና ፡ ዲን ፡ ፴ ዘነበ ፡ ሁሉንም ፡ አጠፋ ። የሰው ፡ ልጅ ፡ በሚ ፴፩ ገለጥበት ፡ ቀን ፡ እንዲሁ ፡ ይሆናል ። በዚያም ፡ ቀን ፡ በሰገነት ፡ ያለ ፡ በቤቱ ፡ ያለውን ፡ ዕቃ ፡ ሊወ ስድ ፡ አይውረድ ፥ እንዲሁም ፡ በእርሻ ፡ ያለ ፡ ፴፪ ወደ ፡ ኋላው ፡ አይመለስ ። የሎጥን ፡ ሚስት ፡ ፴፫ አስቡአት ። ነፍሱን ፡ ሊያድን ፡ የሚፈልግ ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋታል ፥ ነፍሱንም ፡ የሚያጠፋ ፡ ሁሉ ፡ ፴፬ በሕይወት ፡ ይጠብቃታል ። እላችኋለሁ ፥ በዚ ያች ፡ ሌሊት ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ በአንድ ፡ አልጋ ፡ ይሆናሉ ፤ አንዱ ፡ ይወሰዳል ፡ ሁለተኛውም ፡ ፴፭ ይቀራል ። ሁለት ፡ ሴቶች ፡ በአንድ ፡ ወፍጮ ፡ ይፈጫሉ ፤ አንዲቱ ፡ ትወሰዳለች ፡ ሁለተኛይ ፴፮ ቱም ፡ ትቀራለች ። ሁለት ፡ ሰዎች ፡ በእርሻ ፡ ይሆናሉ ፤ አንዱ ፡ ይወሰዳል ፡ ሁለተኛውም ፡ ፴፯ ይቀራል ። መልሰውም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ወዴት ፡ ነው ? አሉት ። እርሱም ፡— ሥጋ ፡ ወዳለበት ፡ በዚያ ፡ አሞራዎች ፡ ይሰበሰባሉ ፡ አላቸው ።

፲፮ ። ፳፱ ፤ ኢሳ. ፰ ፥ ፳ ፤ ዮሐ. ፭ ፥ ፴፱ ። ፴፩ ፤ ማቴ. ፳፰ ፥ ፲፩—፲፭ ፤ ዮሐ. ፲፪ ፥ ፲ ፥ ፲፩ ።

፲፯ ። [illegible]

## ምዕራፍ፡ ፲፰ ።

፩ ሳይታክቱም፡ ዘወትር፡ ሊጸልዩ፡ እንዲገባ ፪ ቸው፡ የሚል፡ ምሳሌን፡ ነገራቸው ፥ እንዲህ፡ ሲል ፦ በአንዲት፡ ከተማ፡ እግዚአብሔርን፡ የማይፈራ፡ ሰውንም፡ የማያፍር፡ አንድ፡ ዳኛ ፫ ነበረ ። በዚያችም፡ ከተማ፡ አንዲት፡ መበለት፡ ነበረች ፥ ወደ፡ እርሱም፡ እየመጣች ፦ ከባላጋ ፬ ራዬ፡ ፍረድልኝ፡ ትለው፡ ነበር ። አያሌ፡ ቀንም፡ አልወደደም ፤ ከዚህ፡ በኋላ፡ ግን፡ በልቡ ፦ ምንም፡ እግዚአብሔርን፡ ባልፈራ፡ ሰውንም፡ ፭ ባላፍር ፥ ይህች፡ መበለት፡ ስለምታደክመኝ፡ ሁልጊዜም፡ እየመጣች፡ እንዳታውከኝ፡ እፈር ፮ ድላታለሁ፡ አለ ። ጌታም፡ አለ ፦ ዓመፀኛው፡ ፯ ዳኛ፡ ያለውን፡ ስሙ ። እግዚአብሔር፡ እንኪ ያስ፡ ቀንና፡ ሌሊት፡ ወደ፡ እርሱ፡ ለሚጮኹ፡ ለሚታገሣቸውም፡ ምርጦቹ፡ አይፈርድላቸው ፰ ምን ? እላችኋለሁ ፥ ፈጥኖ፡ ይፈርድላቸዋል ። ነገር፡ ግን፡ የሰው፡ ልጅ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ በም ድር፡ እምነትን፡ ያገኝ፡ ይሆንን ?

፱ ጻድቃን፡ እንደ፡ ሆኑ፡ በራሳቸው፡ ለሚታ መኑና፡ ሌሎቹን፡ ሁሉ፡ በጣም፡ ለሚንቁ፡ ይህን፡ ፲ ምሳሌ፡ ነገራቸው ፥ እንዲህ፡ ሲል ፦ ሁለት፡ ሰዎች፡ ሊጸልዩ፡ ወደ፡ መቅደስ፡ ወጡ ፥ አንዱ፡ ፲፩ ፈሪሳዊ፡ ሁለተኛውም፡ ቀራጭ ። ፈሪሳዊው፡ ቆሞ፡ በልቡ፡ ይህን፡ ሲጸልይ ፦ እግዚአብሔር፡ ሆይ ፥ እንደ፡ ሌላ፡ ሰው፡ ሁሉ ፥ ቀማኞችና፡ ዓመፀኞች፡ አመንዝሮችም ፥ ወይም፡ እንደዚህ፡ ፲፪ ቀራጭ፡ ስላልሆንሁ፡ አመሰግንሃለሁ ፤ በየሳ ምንቱ፡ ሁለት፡ ጊዜ፡ እጦማለሁ ፥ ከማገኘውም፡ ፲፫ ሁሉ፡ አሥራት፡ አወጣለሁ፡ አለ ። ቀራጩ፡ ግን፡ በሩቅ፡ ቆሞ፡ ዓይኖቹን፡ ወደ፡ ሰማይ፡ ሊያነሣ፡ እንኳ፡ አልወደደም ፥ ነገር፡ ግን ፦ አምላክ፡ ሆይ ፥ እኔን፡ ኃጢአተኛውን፡ ማረኝ፡ ፲፬ እያለ፡ ደረቱን፡ ይደቃ፡ ነበር ። እላችኋለሁ ፥ ከዚያ፡ ይልቅ፡ ይህ፡ ጻድቅ፡ ሆኖ፡ ወደ፡ ቤቱ፡ ተመለሰ ! ራሱን፡ ከፍ፡ የሚያደርግ፡ ሁሉ፡ ይዋረዳልና ፥ ራሱን፡ ግን፡ የሚያዋርድ፡ ከፍ፡ ይላል ።

፲፭ እንዲዳስሳቸውም፡ ሕፃናትን፡ ደግሞ፡ ወደ፡ እርሱ፡ አመጡ ፤ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ አይ ፲፮ ተው፡ ገሠጹአቸው ። ኢየሱስ፡ ግን፡ ሕፃና ትን፡ ወደ፡ እርሱ፡ ጠርቶ ፦ ሕፃናት፡ ወደ፡ እኔ፡ ይመጡ፡ ዘንድ፡ ተዉአቸው፡ አትከልክ ሉአቸውም ፤ የእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ፲፯ እንደ፡ እነዚህ፡ ላሉት፡ ናትና ። እውነት፡ እላች ኋለሁ ፥ የእግዚአብሔርን፡ መንግሥት፡ እንደ፡ ሕፃን፡ የማይቀበላት፡ ሁሉ፡ ከቶ፡ አይገባባትም፡ አለ ።

፲፰ ከአለቆችም፡ አንዱ ፦ ቸር፡ መምህር ፥ የዘ ላለምን፡ ሕይወት፡ እንድወርስ፡ ምን፡ ላድርግ ? ፲፱ ብሎ፡ ጠየቀው ። ኢየሱስም ፦ ስለ፡ ምን፡ ቸር፡ ትለኛለህ ? ከአንዱ፡ ከእግዚአብሔር፡ ፳ በቀር፡ ቸር፡ ማንም፡ የለም ። ትእዛዛቱን፡ ታውቃለህ ፥ አታመንዝር ፥ አትግደል ፥ አትስ ረቅ ፥ በሐሰት፡ አትመስክር ፥ አባትህንና፡ እና ፳፩ ትህን፡ አክብር፡ አለው ። እርሱም ፦ ይህን፡ ሁሉ፡ ከሕፃንነቴ፡ ጀምሬ፡ ጠብቄአለሁ፡ አለ ። ፳፪ ኢየሱስም፡ ይህን፡ ሰምቶ ፦ አንዲት፡ ገና፡ ቀርታሃለች ፤ ያለህን፡ ሁሉ፡ ሽጠህ፡ ለድሆች፡ ስጥ ፥ በሰማይም፡ መዝገብ፡ታገኛለህ ፥ መጥ ፳፫ ተህም፡ ተከተለኝ፡ አለው ። እርሱ፡ ግን፡ ይህን፡ ሰምቶ፡ አዘነ፡ ባለ፡ ጠጋ፡ ነበርና፡ ብዙ፡ ፳፬ አዘነ ። ኢየሱስም፡ ብዙ፡ እንዳዘነ፡ አይቶ ፦ ገንዘብ፡ ላላቸው፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ መን ግሥት፡ መግባት፡ እንዴት፡ጭንቅ፡ ይሆናል ። ፳፭ ባለ፡ ጠጋ፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ከሚገባ፡ ይልቅ፡ ግመል፡ በመርፌ፡ ቀዳዳ፡ ሊገባ፡ ፳፮ ይቀላል፡ አለ ። የሰሙትም ፦ እንግዲህ፡ ማን፡ ፳፯ ሊድን፡ ይችላል ? አሉ ። እርሱ፡ ግን ፦ በሰው፡ ዘንድ፡ የማይቻል፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ይቻ ፳፰ ላል፡ አለ ። ጴጥሮስም ፦ እነሆ ፥ እኛ፡ ሁሉን፡ ፳፱ ትተን፡ ተከተልንህ፡ አለ ። እርሱም ፦ እውነት፡ እላችኋለሁ ፥ ስለ፡ እግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ቤትን፡ ወይም፡ ወላጆችን፡ ወይም፡ ወንድሞ ችን፡ ወይም፡ ሚስትን፡ ወይም፡ ልጆችን፡ ፴ የተወ ፥ በዚህ፡ ዘመን፡ ብዙ፡ እጥፍ፡ በሚመ ጣውም፡ ዓለም፡ የዘላለምን፡ ሕይወት፡ የማይ ቀበል፡ ማንም፡ የለም፡ አላቸው ።

፴፩ አሥራ፡ ሁለቱንም፡ ወደ፡ እርሱ፡ አቅርቦ፡ እንዲህ፡ አላቸው ፦ እነሆ ፥ ወደ፡ ኢየሩሳሌም፡ እንወጣለን ፥ ስለ፡ ሰው፡ ልጅም፡ በነቢያት፡ ፴፪ የተጻፈው፡ ሁሉ፡ ይፈጸማል ። ለአሕዛብ፡ አሳ ልፈው፡ ይሰጡታልና ፥ ይዘብቱበትማል፡ ያንገ ፴፫ ላቱትማል፡ ይተፉበትማል ፤ ከገረፉትም፡ በኋላ፡ ይገድሉታል ፥ በሦስተኛውም፡ ቀን፡ ይነሣል ። ፴፬ እነርሱም፡ ከዚህ፡ ነገር፡ ምንም፡ አላስተዋሉም ፥ ይህም፡ ቃል፡ ተሰውሮባቸው፡ ነበር ፥ የተናገረ ውንም፡ አላወቁም ።

፴፭ ወደ፡ ኢያሪኮም፡ በቀረበ፡ ጊዜ፡ አንድ፡ ዕውር፡ እየለመነ፡ በመንገድ፡ዳር፡ ተቀምጦ፡ ፴፮ ነበር ። ሕዝብም፡ ሲያልፍ፡ ሰምቶ ፦ ይህ፡ ፴፯ ምንድር፡ነው ? ብሎ፡ ጠየቀ ። እነርሱም ፦ የና ዝሬቱ፡ ኢየሱስ፡ ያልፋል፡ ብለው፡ አወሩለት ። ፴፰ እርሱም ፦ የዳዊት፡ ልጅ ፥ ኢየሱስ፡ ሆይ ፥ ፴፱ ማረኝ፡ እያለ፡ ጮኸ ። በስተ፡ ፊት፡ ይሄዱ፡ የነበሩትም፡ ዝም፡ እንዲል፡ ገሠጹት ! እርሱ፡ ግን ፦ የዳዊት፡ ልጅ፡ ሆይ ፥ ማረኝ፡ እያለ፡ አብ ፵ ዝቶ፡ ጮኸ ። ኢየሱስም፡ ቆሞ፡ ወደ፡ እርሱ፡

፲፰። ፩፤ ም. ፲፩፥፭። ፯፤ መዝ. ፱፥፲፪፤ ፻፯፥፩፤ ራእ. ፮፥፲። ፰፤ ም. ፲፯፥፳፮—፴። ፱፤ ም. ፲፮፥፲፭፤ ዮሐ. ፯፥፵፯—፵፱፤ ኢሳ. ፷፭፥፭። ፲፫፤ መዝ. ፶፩፥፲። ፲፬፤ ም. ፲፬፥፲፩። ፲፭—፲፯፤ ማቴ. ፲፱፥፲፫—፲፭፤ ማር. ፲፥፲፫—፲፮። ፲፰—፴፤ ማቴ. ፲፱፥፲፮—፴፤ ማር. ፲፥፲፯—፴። ፳፤ ዘፀ. ፳፥፲፪—፲፮። ፳፪፤ ማቴ. ፮፥፲፱። ፳፬፤ ም. ፳፬፥፳፮። ፳፯፤ ም. ፩፥፴፯። ፴፩—፴፫፤ ማቴ. ፳፥፲፯—፲፱፤ ማር. ፲፥፴፪—፴፬። ፴፬፤ ም. ፱፥፵፭። ፴፭—፵፫፤ ማቴ. ፳፥፳፱—፴፬፤ ማር. ፲፥፵፮—፶፪።

እንዲያመጡት ፡ አዘዘ ። በቀረበም ፡ ጊዜ ፡—
፵፩፡ ምን፡ላደርግልህ፡ትወዳለህ ? ብሎ፡ጠየቀው ።
እርሱም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ አይ፡ዘንድ፡ነው፡አለ ።
፵፪፡ ኢየሱስም ፡— እይ ፤ እምነትህ ፡ አድኖሃል ፡
፵፫፡ አለው ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ አየ ፥ እግዚአብ
ሔርንም ፡ አያከበረ ፡ ተከተለው ። ሕዝቡም ፡
ሁሉ ፡ አይተው ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰገኑ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩፡ ፪፡ ወደ ፡ ኢያሪኮም ፡ ገብቶ ፡ ያልፍ ፡ ነበር ። እነ
ሆም ፡ ዘኬዎስ ፡ የሚባል ፡ ሰው ፥ እርሱም ፡ የቀራ
ጮች ፡ አለቃ ፡ ነበረ ፥ ባለ ፡ ጠጋም ፡ ነበረ ።
፫፡ ኢየሱስንም ፡ የትኛው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሊያይ ፡ ይፈ
ልግ ፡ ነበር ፤ ቁመቱም ፡ አጭር ፡ ነበረና ፡ ስለ ፡
፬፡ ሕዝቡ ፡ ብዛት ፡ አቃተው ። በዚያችም ፡ መን
ገድ ፡ ያልፍ ፡ ዘንድ ፡ አለውና ፡ ያየው ፡ ዘንድ ፡
ወደ ፡ ፊት ፡ ሮጦ ፡ በአንድ ፡ ሾላ ፡ ላይ ፡ ወጣ ።
፭፡ ኢየሱስም ፡ ወደዚያ ፡ ስፍራ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፥
አሻቅቦ ፡ አየና ፡— ዘኬዎስ ፡ ሆይ ፥ ዛሬ ፡ በቤትህ ፡
እውል ፡ ዘንድ ፡ ይገባኛልና ፡ ፈጥነህ ፡ ውረድ ፡
፮፡ አለው ። ፈጥኖም ፡ ወረደ ፡ በደስታም ፡ ተቀበ
፯፡ ለው ። ሁሉም ፡ አይተው ፡— ከኃጢአተኛ ፡
ሰው ፡ ጋር ፡ ሊውል ፡ ገባ ፡ ብለው ፡ አንጐራጐሩ ።
፰፡ ዘኬዎስ ፡ ግን ፡ ቆሞ ፡ ጌታን ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥
ከለኝ ፡ ሁሉ ፡ እኵሌታውን ፡ ለድሆች ፡ እሰጣ
ለሁ ፤ ማንንም ፡ በሐሰት ፡ ከስሼ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡
፱፡ አራት ፡ እጥፍ ፡ እመልሳለሁ ፡ አለው ። ኢየሱ
ስም ፡— እርሱ ፡ ደግሞ ፡ የአብርሃም ፡ ልጅ ፡
ነውና ፡ ዛሬ ፡ ለዚህ ፡ ቤት ፡ መዳን ፡ ሆኖለታል ፤
፲፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ የጠፋውን ፡ ሊፈልግና ፡ ሊያድን ፡
መጥቶአልና ፡ አለው ።
፲፩፡ እነርሱም ፡ ይህን ፡ ሲሰሙ ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
መቅረቡ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የእግዚአብሔርም ፡ መንግ
ሥት ፡ ፈጥኖ ፡ ሊገለጥ ፡ እንዳለው ፡ ስለ ፡ መሰላ
፲፪፡ ቸው ፡ ምሳሌ ፡ ጨምሮ ፡ ተናገረ ። ስለዚህም ፡ እን
ዲህ ፡ አላቸው ፡— አንድ ፡ መኰንን ፡ ለራሱ ፡ መንግ
ሥትን ፡ ይዞ ፡ ሊመለስ ፡ ወደ ፡ ሩቅ ፡ አገር ፡ ሄደ ።
፲፫፡ አሥር ፡ ባሪያዎችንም ፡ ጠርቶ ፡ አሥር ፡ ምናን ፡ ሰጣ
ቸውና ፡— እስክመጣ ፡ ድረስ ፡ ነግዱ ፡ አላቸው ።
፲፬፡ የአገሩ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ይጠሉት ፡ ነበርና ፡— ይህ ፡
በላያችን ፡ ሊነግሥ ፡ አንወድም ፡ ብለው ፡ በኋ
፲፭፡ ላው ፡ መልክተኞችን ፡ላኩ ። መንግሥትንም ፡
ይዞ ፡ በተመለሰ ፡ ጊዜ ፥ ገንዘብ ፡ የሰጣቸውን ፡
እነዚህን ፡ ባሪያዎች ፡ ነግደው ፡ ምን ፡ ያህል ፡ እንዳ
ተረፉ ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፡ እንዲጠሩለት ፡ አዘዘ ።
፲፮፡ የፊተኛውም ፡ ደርሶ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ምናንህ ፡
፲፯፡ አሥር ፡ ምናን ፡ አተረፈ ፡ አለው ። እርሱም ፡—
መልካም ፥ አንተ ፡ በጎ ፡ ባርያ ፥ በጥቂት ፡ የታ
መንህ ፡ ስለ ፡ ሆንህ ፡ በአሥር ፡ ከተማዎች ፡ ላይ ፡
፲፰፡ ሥልጣን ፡ ይሁንልህ ፡ አለው ። ሁለተኛውም ፡
መጥቶ ፡ — ጌታ ፡ ሆይ ፥ ምናንህ ፡ አምስት ፡ ምናን ፡
፲፱፡ አተረፈ ፡ አለው ። ይህንም ፡ ደግሞ ፡— አንተም ፡
በአምስት ፡ ከተማዎች ፡ ላይ ፡ ሁን ፡ አለው ።
፳፡ ሌላውም ፡ መጥቶ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ በጨርቅ ፡
፳፩፡ ጠቅልዬ ፡ የጠበቅኋት ፡ ምናንህ ፡ እነሆ ፤ ፈርቼ
ሃለሁና ፥ ጨካኝ ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ ሆንህ ፤ ያላኖርኸ
ውን ፡ ትወስዳለህ ፡ ያልዘራኸውንም ፡ ታጭዳ
፳፪፡ ለህ ፡ አለው ። እርሱም ፡— አንተ ፡ ክፉ ፡ ባሪያ ፥
አፍህ ፡ በተናገረው ፡ እፈርድብሃለሁ ። እኔ ፡
ያላኖርሁትን ፡ የምወስድና ፡ ያልዘራሁትን ፡ የማ
ጭድ ፡ ጨካኝ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ አወቅህ ፤
፳፫፡ ምን ፡ ነው ፡ ገንዘቤን ፡ ለለዋጮች ፡ አደራ ፡ ያልሰ
ጠኸው ? እኔም ፡ መጥቼ ፡ ከትርፉ ፡ ጋር ፡ አወስ
፳፬፡ ደው ፡ ነበር ፡ አለው ። በዚያም ፡ ቆመው ፡ የነ
በሩትን ፡— ምናኑን ፡ ውሰዱበት ፡ አሥሩ ፡ ምናን ፡
፳፭፡ ላለውም ፡ ስጡት ፡ አላቸው ። እነርሱም ፡—
፳፮፡ ጌታ ፡ ሆይ ፥ አሥር ፡ ምናን ፡ አለው ፡ አሉት ። እላ
ችኋለሁ ፥ ላለው ፡ ሁሉ ፡ ይሰጠዋል ፥ ከሌለው ፡
ግን ፡ ያው ፡ ያለው ፡ በንኳ ፡ ይወሰድበታል ።
፳፯፡ ነገር ፡ ግን ፡ እነዚያን ፡ በላያቸው ፡ ልነግሥ ፡ ያል
ወደዱትን ፡ ጠላቶቼን ፡ ወደዚህ ፡ አምጡአቸው ፡
በፊቴም ፡ አረዱአቸው ።
፳፰፡ ይህንም ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳ
፳፱፡ ሌም ፡ ሲወጣ ፡ ይቀድማቸው ፡ ነበር ። ደብረ ፡
ዘይትም ፡ በሚባል ፡ ተራራ ፡ አጠገብ ፡ ወዳሉት ፡
ወደ ፡ ቤተ ፡ ፋጌና ፡ ወደ ፡ ቢታንያ ፡ በቀረበ ፡
ጊዜ ፥ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ሁለቱን ፡ ላከና ፡—
፴፡ በፊታችሁ ፡ ወዳለችው ፡ መንደር ፡ ሂዱ ፥ ወደ ፡
እርስዋም ፡ ገብታችሁ ፡ ከሰው ፡ ማንም ፡ ገና ፡
ያልተቀመጠበት ፡ ውርንጫ ፡ ታስሮ ፡ ታገኛ
፴፩፡ ላችሁ ፥ ፈትታችሁም ፡ አምጡት ። ማንም ፡—
ስለ ፡ ምን ፡ ትፈቱታላችሁ ? ብሎ ፡ ቢጠይቃ
ችሁ ፥ እንዲሁ ፡— ለጌታ ፡ ያስፈልገዋል ፡ በሉ ፡
፴፪፡ አላቸው ። የተላኩትም ፡ ሄደው ፡ እንዳላቸው ፡
፴፫፡ አገኙ ። እነርሱም ፡ ውርንጫውን ፡ ሲፈቱ ፡
ጌቶቹ ፡— ውርንጫውን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትፈቱታ
፴፬፡ ላችሁ ? አሉአቸው ። እነርሱም ፡— ለጌታ ፡
፴፭፡ ያስፈልገዋል ፡ አሉ ። ወደ ፡ ኢየሱስም ፡ አመ
ጡት ፥ በውርንጫውም ፡ ላይ ፡ ልብሳቸውን ፡
፴፮፡ ጭነው ፡ ኢየሱስን ፡ አስቀመጡት ። ሲሄድም ፡
፴፯፡ ልብሳቸውን ፡ በመንገድ ፡ ያነጥፉ ፡ ነበር ። ወደ ፡
ደብረ ፡ ዘይት ፡ ቍልቍለትም ፡ አሁን ፡ በቀረበ ፡
ጊዜ ፥ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ሁላቸው ፡ ደስ ፡ እያላ
ቸው ፡ ተአምራትን ፡ ሁሉ ፡ ስላዩ ፡ በታላቅ ፡
ድምፅ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ሊያመሰግኑ ፡ ጀም
፴፰፡ ረው ፡— በጌታ ፡ ስም ፡ የሚመጣ ፡ ንጉሥ ፡ የተ
ባረከ ፡ ነው ፤ በሰማይ ፡ ሰላም ፡ በአርያምም ፡
፴፱፡ ክብር ፡ አሉ ። ከሕዝብም ፡ መካከል ፡ ከፈሪሳው
ያን ፡ አንዳንዱ ፡— መምህር ፡ ሆይ ፥ ደቀ ፡ መዛ
፵፡ ሙርትህን ፡ ገሥጻቸው ፡ አሉት ። መልሶም ፡—

አላችኋለሁ ፥ እነዚህ ፡ ዝም ፡ ቢሉ ፡ ድንጋዮች ፡ ይጮኻሉ ፡ አላቸው ።

፵፩ ሲቀርብም ፡ ከተማይቱን ፡ አይቶ ፡ አለቀሰላት ፥ ፵፪ እንዲህ ፡ እያለ ፦ ለሰላምሽ ፡ የሚሆነውን ፡ በዚህ ፡ ቀን ፡ አንቺስ ፡ ስንኳ ፡ ብታውቂ ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ፵፫ ከዓይንሽ ፡ ተሰውሮአል ። ወራት ፡ ይመጣብሻልና ፥ ጠላቶችሽም ፡ ቅጥር ፡ ይቀጥሩብሻል ፡ ይከ ፵፬ ቡሻልም ፡ በየበኩሉም ፡ ያስጨንቁሻል ፤ አንቺንም ፡ በአንቺም ፡ ውስጥ ፡ የሚኖሩትን ፡ ልጆችሽን ፡ ወደ ፡ ታች ፡ ይጥላሉ ፥ በአንቺ ፡ ውስጥም ፡ ድንጋይ ፡ በድንጋይ ፡ ላይ ፡ አይተዉም ፥ የመጐብኘትሽን ፡ ዘመን ፡ አላወቅሽምና ።

፵፭ ወደ ፡ መቅደስም ፡ ገብቶ ፡ በእርሱ ፡ የሚሸጡ ፵፮ ትን ፡ የሚገዙትንም ፡ ያወጣ ፡ ጀመር ፤ እርሱም ፦ ቤቴ ፡ የጸሎት ፡ ቤት ፡ ይሆናል ፡ ተብሎ ፡ ተጽፎአል ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ የወንበዴዎች ፡ ዋሻ ፡ አደረጋችሁት ፡ አላቸው ።

፵፯ ዕለት ፡ ዕለትም ፡ በመቅደስ ፡ ያስተምር ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የካህናት ፡ አለቆችና ፡ ጻፎች ፡ የሕዝቡ ፡ ታላላቆችም ፡ ሊገድሉት ፡ ይፈልጉ ፡ ነበር ፥ ፵፰ የሚያደርጉበትንም ፡ አጡ ፤ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ሲሰሙት ፡ ተንጠልጥለውበት ፡ ነበርና ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ አንድ ፡ ቀንም ፡ ሕዝቡን ፡ በመቅደስ ፡ ሲያስተምር ፡ ወንጌልንም ፡ ሲሰብክላቸው ፥ የካህናት ፡ አለቆችና ፡ ጻፎች ፡ ከሽማግሌዎች ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ፪ እርሱ ፡ ቀረቡና ፦ እስኪ ፡ ንገረን ፤ እነዚህን ፡ በምን ፡ ሥልጣን ፡ ታደርጋለህ ፡ ወይስ ፡ ይህን ፡ ሥልጣን ፡ የሰጠህ ፡ ማን ፡ ነው ? ብለው ፡ ተናገ ፫ ሩት ። መልሶም ፦ እኔ ፡ ደግሞ ፡ አንዲት ፡ ነገር ፡ ፬ እጠይቃችኋለሁ ፥ እናንተም ፡ ንገሩኝ ፤ የዮሐንስ ፡ ጥምቀት ፡ ከሰማይ ፡ ነበረችን ፡ ወይስ ፡ ፭ ከሰው ? አላቸው ። እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ ሲነጋገሩ ፦ ከሰማይ ፡ ብንል ፦ ስለ ፡ ምን ፡ አላመ ፮ ናችሁበትም ? ይለናል ፤ ከሰው ፡ ብንል ፡ ግን ፥ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ይወግሩናል ፤ ዮሐንስ ፡ ነቢይ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ሁሉ ፡ ያምኑ ፡ ነበርና ፡ አሉ ። ፯ መልሰውም ፦ ከወዴት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አናው ፰ ቅም ፡ አሉት ። ኢየሱስም ፦ እኔም ፡ በምን ፡ ሥልጣን ፡ እነዚህን ፡ እንዳደርግ ፡ አልነግራችሁም ፡ አላቸው ።

፱ ይህንም ፡ ምሳሌ ፡ ለሕዝቡ ፡ ይላቸው ፡ ጀመር ። አንድ ፡ ሰው ፡ የወይን ፡ አትክልት ፡ተከለ ፡ ለገበሬዎችም ፡ አከራይቶ ፡ ለብዙ ፡ ዘመን ፡ ወደ ፡ ፲ ሌላ ፡ አገር ፡ ሄደ ። በጊዜውም ፡ ከወይኑ ፡ አትክልት ፡ ፍሬ ፡ እንዲሰጡት ፡ አንድ ፡ ባሪያ ፡ ወደ ፡ ገበሬዎች ፡ላከ ፤ ገበሬዎቹ ፡ ግን ፡ ደበደቡት ፡ ፲፩ ባዶውንም ፡ ሰደዱት ። ጨምሮም ፡ ሌላውን ፡ ባሪያ ፡ ላከ ፤ እነርሱም ፡ ያን ፡ ደግሞ ፡ ደበደቡት ፡ ፲፪ አዋርደውም ፡ ባዶውን ፡ ሰደዱት ። ጨምሮም ፡ ሦስተኛውን ፡ ላከ ፤ እነርሱም ፡ ይህን ፡ ደግሞ ፡ ፲፫ አቍስለው ፡ አወጡት ። የወይኑም ፡ አትክልት ፡ ጌታ ፦ ምን ፡ ላድርግ ? የምወደውን ፡ ልጄን ፡ እልካለሁ ፤ ምናልባት ፡ እርሱን ፡ አይተው ፡ ያፍ ፲፬ ሩታል ፡ አለ ። ገበሬዎቹ ፡ ግን ፡ አይተውት ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ሲነጋገሩ ፦ ወራሹ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ርስቱ ፡ ለእኛ ፡ እንዲሆን ፡ ኑ ፡ እንግደለው ፡ ፲፭ አሉ ። ከወይኑም ፡ አትክልት ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አውጥተው ፡ ገደሉት ። እንግዲህ ፡ የወይኑ ፡ ፲፮ አትክልት ፡ ጌታ ፡ ምን ፡ ያደርጋቸዋል ? ይመጣል ፡ እነዚህንም ፡ ገበሬዎች ፡ ያጠፋል ፥ የወይኑንም ፡ አትክልት ፡ ለሌሎች ፡ ይሰጣል ። ይህንም ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፦ ይህስ ፡ አይሁን ፡ አሉ ። ፲፯ እርሱ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ተመልክቶ ፦ እንግዲህ ፦

ግንበኞች ፡ የናቁት ፡ ድንጋይ ፡ እርሱ ፡ የማዕዘን ፡ ራስ ፡ ሆነ ፡

፲፰ ተብሎ ፡ የተጻፈው ፡ ይህ ፡ ምንድር ፡ ነው ? በዚያም ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ የሚወድቅ ፡ ሁሉ ፡ ይቀጠቀጣል ፤ የሚወድቅበትን ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ይፈጨዋል ፡ አለ ።

፲፱ የካህናት ፡ አለቆችና ፡ ጻፎችም ፡ ይህን ፡ ምሳሌ ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ አውቀው ፡ በዚያች ፡ ሰዓት ፡ እጃቸውን ፡ ሊጭኑበት ፡ ፈለጉ ፡ ፳ ነገር ፡ ግን ፡ ሕዝቡን ፡ ፈሩ ። ሲጠባበቁም ፡ ወደ ፡ ገዢ ፡ ግዛትና ፡ ሥልጣን ፡ አሳልፈው ፡ እንዲሰጡት ፡ ጻድቃን ፡ መስለው ፡ በቃሉ ፡ የሚያጠምዱትን ፡ ሸማቂዎች ፡ ሰደዱበት ። ጠየቁትም ፦ ፳፩ መምህር ፡ ሆይ ፥ እውነትን ፡ እንድትናገርና ፡ እንድታስተምር ፡ ለሰው ፡ ፊትም ፡ እንዳታደላ ፡ እናውቃለን ፥ በእውነት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንገድ ፡ ታስተምራለህ ፡ አንጂ ፤ ለቄሣር ፡ ፳፪ ግብር ፡ ልንሰጥ ፡ ተፈቅዶልናል ? ወይስ ፡ አልተፈቀደም ? አሉት ። እርሱ ፡ ግን ፡ ተንኰላቸውን ፡ ፳፫ ተመልክቶ ፦ ስለ ፡ ምን ፡ ትፈትኑኛላችሁ ? ፳፬ አንድ ፡ ዲናር ፡ አሳዩኝ ፤ መልኩ ፡ ጽሕፈቱስ ፡ የማን ፡ ነው ? አላቸው ። መልሰውም ፦ የቄ ፳፭ ሣር ፡ ነው ፡ አሉት ። እርሱም ፦ እንኪያስ ፡ የቄሣርን ፡ ለቄሣር ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አስረክቡ ፡ አላቸው ። ፳፮ በሕዝቡም ፡ ፊት ፡ በቃሉ ፡ ሊያጠምዱት ፡ አልቻሉም ፡ በመልሱም ፡ እየተደነቁ ፡ ዝም ፡ አሉ ።

፳፯ ትንሣኤ ፡ ሙታንንም ፡ የሚክዱ ፡ ከሰዱቃው ፳፰ ያን ፡ አንዳንዶቹ ፡ ቀርበው ፡ ጠየቁት ፥ እንዲህ ፡ ሲሉ ፦ መምህር ፡ ሆይ ፥ ሙሴ ፦ ሚስት ፡ ያለ

፲፱ ። ፵፫—፵፬ ፤ ም. ፲፫ ፥ ፴፬ ፡ ፴፭ ። ፵፫ ፤ ኢሳ. ፳፱ ፥ ፫ ። ፵፬ ፤ ም. ፳፩ ፥ ፮ ፤ ፩ ፥ ፸፰ ። ፵፭ ፡ ፵፮ ፤ ማቴ. ፳፩ ፥ ፲፪ ፡ ፲፫ ፤ ማር. ፲፩ ፥ ፲፭—፲፯ ፤ ዮሐ. ፪ ፥ ፲፬—፲፮ ። ፵፮ ፤ ኢሳ. ፶፮ ፥ ፯ ፤ ኤር. ፯ ፥ ፲፩ ። ፵፯ ፡ ፵፰ ፤ ማር. ፲፩ ፥ ፲፰ ።
፳ ። ፩—፰ ፤ ማቴ. ፳፩ ፥ ፳፫—፳፯ ፤ ማር. ፲፩ ፥ ፳፯—፴፫ ። ፱—፲፱ ፤ ማቴ. ፳፩ ፥ ፴፫—፵፮ ፤ ማር. ፲፪ ፥ ፩—፲፪ ፤ መዝ. ፹ ፥ ፰ ፤ ኢሳ. ፭ ፥ ፩ ። ፯ ፤ ፪ ዜና ፴፮ ፥ ፲፭ ፡ ፲፮ ። ፲፯ ፤ መዝ. ፻፲፰ ፥ ፳፪ ። ፲፰ ፤ ኢሳ. ፰ ፥ ፲፬ ፡ ፲፭ ፤ ዳን. ፪ ፥ ፴፬ ፡ ፵፬ ። ፲፱ ፤ ማቴ. ፳፩ ፥ ፵፭ ፡ ፵፮ ። ፳—፳፮ ፤ ማቴ. ፳፪ ፥ ፲፭—፳፪ ፤ ማር. ፲፪ ፥ ፲፫—፲፯ ። ፳ ፤ ም. ፮ ፥ ፯ ። ፳፭ ፤ ሮሜ. ፲፫ ፥ ፯ ።

ችው ፡ የአንድ ፡ ሰው ፡ ወንድም ፡ ልጅ ፡ ሳይወ
ልድ ፡ ቢሞት ፥ ወንድሙ ፡ ሚስቱን ፡ አግብቶ ፡
፳፱ ለወንድሙ ፡ ዘር ፡ ይተካ ፡ ብሎ ፡ ጻፈልን ። እን
ግዲያስ ፡ ሰባት ፡ ወንድማማች ፡ ነበሩ ፤ የፊተ
ኛውም ፡ ሚስት ፡ አግብቶ ፡ ልጅ ፡ ሳይወልድ ፡
፴፡፴፩ ሞተ ፤ ሁለተኛውም ፡ አገባት ፥ ሦስተኛውም ፥
እንዲሁም ፡ ሰባቱ ፡ ደግሞ ፡ ልጅ ፡ ሳይተዉ ፡
፴፪ ሞቱ ። ከሁሉም ፡ በኋላ ፡ ሴቲቱ ፡ ደግሞ ፡
፴፫ ሞተች ። እንግዲህ ፡ ሰባቱ ፡ አግብተዋታልና ፡
ሴቲቱ ፡ በትንሣኤ ፡ ከእነርሱ ፡ ለማንኛቸው ፡
ሚስት ፡ ትሆናለች ?

፴፬ ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦
የዚህ ፡ ዓለም ፡ ልጆች ፡ ያገባሉ ፡ ይጋባሉም ፥
፴፭ ያን ፡ ዓለምና ፡ ከሙታን ፡ ትንሣኤ ፡ ሊያገኙ ፡
የሚገባቸው ፡ እነዚያ ፡ ግን ፡ አያገቡም ፡ አይ
፴፮ ጋቡምም ፥ እንደ ፡ መላእክት ፡ ናቸውና ፥ ሊሞ
ቱም ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ አይቻላቸውም ፤ የትንሣኤም ፡
ልጆች ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡
፴፯ ናቸው ። ሙታን ፡ እንዲነሡ ፡ ግን ፡ ሙሴ ፡
ደግሞ ፡ በቍጥቋጦው ፡ ዘንድ ፡ ጌታን ፡ የአብር
ሃም ፡ አምላክ ፡ የይስሐቅም ፡ አምላክ ፡ የያዕቆ
፴፰ ብም ፡ አምላክ ፡ በማለቱ ፡ አስታወቀ ፤ ሁሉ ፡ ለእ
ርሱ ፡ ሕያዋን ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፥ የሕያዋን ፡ አምላክ ፡
፴፱ ነው ፡ እንጂ ፡ የሙታን ፡ አይደለም ። ከጻፎችም ፡
አንዳንዶቹ ፡ መልሰው ፦ መምህር ፡ ሆይ ፥
፵ መልካም ፡ ተናገርህ ፡ አሉት ። ወደ ፡ ፊትም ፡
አንድ ፡ ነገር ፡ ስንኳ ፡ ሊጠይቁት ፡ አልደፈሩም ።

፵፩ እንዲህም ፡ አላቸው ፦ ክርስቶስ ፡ የዳዊት ፡
፵፪፡፵፫ ልጅ ፡ ነው ፡ እንዴት ፡ ይላሉ ? ዳዊትም ፡ ራሱ ፡
በመዝሙራት ፡ መጽሐፍ ፦

ጌታ ፡ ጌታዬን ፦ ጠላቶችህን ፡ ለእግርህ ፡
መርገጫ ፡ እስካደርግልህ ፡ ድረስ ፡ በቀኜ ፡
ተቀመጥ ፡ አለው ፡

፵፬ ይላል ። እንግዲህ ፡ ዳዊት ፦ ጌታ ፡ ብሎ ፡ ይጠ
ራዋል ፥ እንዴትስ ፡ ልጁ ፡ ይሆናል ?

፵፭ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ሲሰሙ ፡ ደቀ ፡ መዛሙር
፵፮ ቱን ፦ ረጃጅም ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡ መዞር ፡ ከሚ
ፈልጉ ፥ በገበያም ፡ ሰላምታ ፥ በምኵራብም ፡ የከ
በሬታ ፡ ወንበር ፥ በምሳም ፡ የከበሬታ ፡ ስፍራ ፡
፵፯ ከሚወዱ ፡ ከጻፎች ፡ ተጠበቁ ፤ የመበለቶችን ፡
ቤት ፡ የሚበሉ ፡ ጸሎታቸውንም ፡ በማስረዘም ፡
የሚያመካኙ ፥ እነዚህ ፡ የባሰ ፡ ፍርድ ፡ ይቀበ
ላሉ ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ ዓይኑንም ፡ አንሥቶ ፡ መባቸውን ፡ በመዝገብ ፡
፪ የሚጥሉ ፡ ባለ ፡ ጠጎችን ፡ አየ ። አንዲትም ፡ ድሀ ፡
መበለት ፡ ሁለት ፡ ሳንቲም ፡ በዚያ ፡ ስትጥል ፡
፫ አየና ፦ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ይህች ፡ ድሀ ፡
መበለት ፡ ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ አብልጣ ፡ ጣለች ፤
፬ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ከትርፋቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ መዝገብ ፡ ጥለዋልና ፤ ይህች ፡ ግን ፡ ከጕ
ድለትዋ ፡ የነበራትን ፡ ትዳርዋን ፡ ሁሉ ፡ ጣለች ፡
አለ ።

፭ አንዳንዶቹም ፡ ስለ ፡ መቅደስ ፡ በመልካም ፡ ድን
ጋይና ፡ በተሰጠው ፡ ሽልማት ፡ እንዳጌጠ ፡ ሲነ
፮ ጋገሩ ፦ ይህማ ፡ የምታዩት ፡ ሁሉ ፥ ድንጋይ ፡
በድንጋይ ፡ ላይ ፡ ሳይፈርስ ፡ በዚህ ፡ የማይቀርበት ፡
፯ ዘመን ፡ ይመጣል ፡ አለ ። እነርሱም ፦ መም
ህር ፡ ሆይ ፥ እንግዲህ ፡ ይህ ፡ መቼ ፡ ይሆናል ?
ይህስ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ እንዳለው ፡ ምልክቱ ፡
፰ ምንድር ፡ ነው ? ብለው ፡ ጠየቁት ። እንዲህም ፡
አለ ፦ እንዳትስቱ ፡ ተጠንቀቁ ፤ ብዙዎች ፦
እኔ ፡ ነኝ ፥ ዘመኑም ፡ ቀርቦአል ፡ እያሉ ፡ በስሜ ፡
ይመጣሉና ፤ እነርሱን ፡ ተከትላችሁ ፡ አትሂዱ ።
፱ ጦርነትና ፡ ሁከትንም ፡ በሰማችሁ ፡ ጊዜ ፡ አትደ
ንግጡ ፤ ይህ ፡ አስቀድሞ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ግድ ፡
ነውና ፥ ነገር ፡ ግን ፡ መጨረሻው ፡ ወዲያው ፡ አይ
ሆንም ።

፲ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ ሕዝብ ፡
በሕዝብ ፡ ላይ ፥ መንግሥትም ፡ በመንግሥት ፡
፲፩ ላይ ፡ ይነሣል ፤ ታላቅም ፡ የምድር ፡ መናወ
ጥና ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ስፍራ ፡ ቸነፈር ፡ ራብም ፡
ይሆናል ፤ የሚያስፈራም ፡ ነገር ፡ ከሰማይም ፡
፲፪ ታላቅ ፡ ምልክት ፡ ይሆናል ። ከዚህም ፡ ሁሉ ፡
በፊት ፡ እጃቸውን ፡ በላያችሁ ፡ ይጭናሉ ፡ ያሳ
ድዱአችሁማል ፤ ስለ ፡ ስሜም ፡ ወደ ፡ ምኵራ
ብና ፡ ወደ ፡ ወኅኒ ፡ አሳልፈው ፡ ይሰጡአችኋል ፥
ወደ ፡ ነገሥታትና ፡ ወደ ፡ ገዥዎችም ፡ ይወስዱ
፲፫ አችኋል ፤ ይህም ፡ ለምስክርነት ፡ ይሆንላችኋል ።
፲፬ ስለዚህ ፡ እንዴት ፡ እንድትመልሱ ፡ አስቀድማ
፲፭ ችሁ ፡ እንዳታስቡ ፡ በልባችሁ ፡ አኑሩት ፤ ወደ
ረኞቻችሁ ፡ ሁሉ ፡ ሊቃወሙና ፡ ሊከራከሩ ፡ የማ
ይችሉትን ፡ አፍና ፡ ጥበብ ፡ እሰጣችኋለሁና ።
፲፮ ወላጆችም ፡ ስንኳ ፡ ወንድሞችም ፡ ዘመዶችም ፡
ወዳጆችም ፡ አሳልፈው ፡ ይሰጡአችኋል ፥ ከእ
፲፯ ናንተም ፡ አንዳንዱን ፡ ይገድላሉ ፤ በሁሉም ፡
፲፰ ስለ ፡ ስሜ ፡ የተጠላችሁ ፡ ትሆናላችሁ ። ከራስ
ችሁም ፡ አንዲት ፡ ጠጕር ፡ ስንኳ ፡ አትጠፋም ፤
፲፱ በመታገሣችሁም ፡ ነፍሳችሁን ፡ ታገኛላችሁ ።

፳ ኢየሩሳሌም ፡ ግን ፡ በጭፍራ ፡ ተከባ ፡ ስታዩ ፡
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ጥፋትዋ ፡ እንደ ፡ ቀረበ ፡ እወቁ ።
፳፩ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ በይሁዳ ፡ ያሉ ፡ ወደ ፡ ተራራዎች ፡
ይሽሹ ፥ በመካከልዋም ፡ ያሉ ፡ ከእርስዋ ፡ ፈቀቅ ፡
ይበሉ ፥ በገጠር ፡ ያሉም ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ አይ
፳፪ ግቡ ፤ የተጻፈው ፡ ሁሉ ፡ እንዲፈጸም ፡ ይህ ፡
፳፫ የበቀል ፡ ጊዜ ፡ ነውና ። በዚያን ፡ ወራት ፡ ለእ
ርጕዞችና ፡ ለሚያጠቡ ፡ ወዮላቸው ፤ ታላቅ ፡

፳ ። ፴፯ ፤ ፩ ቆሮ. ፲፭ ፥ ፶፫ ፡ ፶፬ ። ፴፯ ፤ ዘፀአ. ፫ ፥ ፮—፯ ። ፵፩—፵፬ ፤ ማቴ. ፳፪ ፥ ፵፩—፵፮ ፤ ማር. ፲፪ ፥ ፴፭—፴፯ ። ፵፪ ፤ መዝ. ፻፲ ፥ ፩ ። ፵፭—፵፯ ፤ ም. ፲፩ ፥ ፵፫ ፤ ማቴ. ፳፫ ፥ ፩ ፤ ፭—፯ ፤ ፲፬ ፤ ማር. ፲፪ ፥ ፴፰—፵ ።

፳፩ ። ፩—፬ ፤ ፪ ነገሥ. ፲፪ ፥ ፲ ፤ ማር. ፲፪ ፥ ፵፩—፵፬ ። ፭—፴፮ ፤ ማቴ. ፳፬ ፥ ፩—፶፩ ፤ ማር. ፲፫ ፥ ፩—፴፯ ። ፰ ፤ ም. ፲፯ ፥ ፳፫ ፡ ፳፬ ። ፲፪—፲፯ ፤ ማቴ. ፲ ፥ ፲፯—፳፪ ። ፲፬ ፤ ም. ፲፪ ፥ ፲፩ ። ፲፯ ፤ ዮሐ. ፲፭ ፥ ፲፰ ፡ ፲፱ ። ፲፰ ፤ ም. ፲፪ ፥ ፯ ። ፳፪ ፤ ሆሴ. ፱ ፥ ፯ ። ፳፬ ፤ ም. ፲፱ ፥ ፵፬ ።

ችግር ፡ በምድር ፡ ላይ ፥ በዚህም ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ ቍጣ ፡ ይሆናልና ፤ ፳፬ በሰይፍ ፡ ስለትም ፡ ይወድቃሉ ፤ ወደ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉም ፡ ይማረካሉ ፤ የአሕዛብም ፡ ዘመን ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በአሕዛብ ፡ የተረገጠች ፡ ትሆናለች ።

፳፭ በፀሐይና ፡ በጨረቃም ፡ በከዋክብትም ፡ ምልክት ፡ ይሆናል ፤ በምድር ፡ ላይም ፡ አሕዛብ ፡ ከባሕሩና ፡ ከሞገዱም ፡ ድምፅ ፡ የተነሣ ፡ እያመነቱ ፡ ፳፮ ይጨነቃሉ ፤ ሰዎችም ፡ ከፍርሃትና ፡ በዓለም ፡ የሚመጣበትን ፡ ከመጠበቅ ፡ የተነሣ ፡ ይደክማሉ ፤ ፳፯ የሰማያት ፡ ኃይላት ፡ ይናወጣሉና ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በኃይልና ፡ በብዙ ፡ ፳፰ ክብር ፡ በደመና ፡ ሲመጣ ፡ ያዩታል ። ይህም ፡ ሊሆን ፡ ሲጀምር ፡ ቤዛችሁ ፡ ቀርቦአልና ፡ አሻቅባችሁ ፡ ራሳችሁን ፡ አንሡ ።

፳፱ ምሳሌንም ፡ ነገራቸው ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፦ በለ ፴ ስንና ፡ ዛፎችን ፡ ሁሉ ፡ እዩ ፤ ሲያቈጠቍጡ ፡ ተመልክታችሁ ፡ በጋ ፡ አሁን ፡ እንደ ፡ ቀረበ ፡ ፴፩ ራሳችሁ ፡ ታውቃላችሁ ። እንዲሁ ፡ ደግሞ ፡ እናንተ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ መሆኑን ፡ ስታዩ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ እንደ ፡ ቀረበች ፡ እወቁ ። ፴፪ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ይህ ፡ ሁሉ ፡ እስኪሆን ፡ ፴፫ ድረስ ፡ ይህ ፡ ትውልድ ፡ አያልፍም ። ሰማይና ፡ ምድር ፡ ያልፋሉ ፡ ቃሌ ፡ ግን ፡ አያልፍም ።

፴፬ ነገር ፡ ግን ፡ ልባችሁ ፡ በመጠጥ ፡ ብዛትና ፡ በስካር ፡ ስለ ፡ ትዳርም ፡ በማሰብ ፡ እንዳይከብድ ፥ ያ ፡ ቀንም ፡ በድንገት ፡ እንዳይመጣባችሁ ፡ ለራ ፴፭ ሳችሁ ፡ ተጠንቀቁ ፤ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በሚቀመጡ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ወጥመድ ፡ ይደርስባቸ ፴፮ ዋልና ። እንግዲህ ፡ ሊመጣ ፡ ካለው ፡ ከዚህ ፡ ሁሉ ፡ ለማምለጥ ፥ በሰው ፡ ልጅም ፡ ፊት ፡ ለመቆም ፡ እንድትችሉ ፡ ስትጸልዩ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ትጉ ።

፴፯ ዕለት ፡ ዕለትም ፡ በመቅደስ ፡ ያስተምር ፡ ነበር ፤ ሌሊት ፡ ግን ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡ ወደምትባል ፡ ፴፰ ተራራ ፡ ወጥቶ ፡ ያድር ፡ ነበር ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ይሰሙት ፡ ዘንድ ፡ ማልደው ፡ በመቅደስ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ይመጡ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ ፋሲካም ፡ የሚባለው ፡ የቂጣ ፡ በዓል ፡ ቀረበ ። ፪ የካህናት ፡ አለቆችና ፡ ጻፎችም ፡ እንዴት ፡ እንዲያጠፉት ፡ ይፈልጉ ፡ ነበር ፤ ሕዝቡን ፡ ይፈሩ ፡ ነበርና ።

፫ ሰይጣንም ፡ ከአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ቍጥር ፡ አንዱ ፡ ለነበረው ፡ የአስቆሮቱ ፡ በሚባለው ፡ በይሁዳ ፡ ፬ ገባ ፤ ሄዶም ፡ እንዴት ፡ አሳልፎ ፡ እንዲሰጣቸው ፡ ከካህናት ፡ አለቆችና ፡ ከመቅደስ ፡ አዛዦች ፡ ጋር ፡ ተነጋገረ ። ፭ እነርሱም ፡ ደስ ፡ አላቸው ፥ ገንዘ ፮ ብም ፡ ሊሰጡት ፡ ተዋዋሉ ። እሺም ፡ አለ ፥ ሕዝብም ፡ በሌለበት ፡ አሳልፎ ፡ እንዲሰጣቸው ፡ ምቹ ፡ ጊዜ ፡ ይፈልግ ፡ ነበር ።

፯ ፋሲካንም ፡ ሊያርዱበት ፡ የሚገባው ፡ የቂጣ ፡ ፰ በዓል ፡ ደረሰ ፤ ጴጥሮስንና ፡ ዮሐንስንም ፦ ፋሲካን ፡ እንድንበላ ፡ ሄዳችሁ ፡ አዘጋጁልን ፡ ብሎ ፡ ፱ ላካቸው ። እነርሱም ፦ ወዴት ፡ እናዘጋጅ ፡ ፲ ዘንድ ፡ ትወዳለህ ? አሉት ። እርሱም ፡ አላቸው ፦ እነሆ ፥ ወደ ፡ ከተማ ፡ ስትገቡ ፡ ማድጋ ፡ ውኃ ፡ የተሸከመ ፡ ሰው ፡ ይገናኛችኋል ፤ ወደ ፲፩ ሚገባበት ፡ ቤት ፡ ተከተሉት ፤ ለባለቤቱም ፦ መምህሩ ፦ ከደቀ ፡ መዛሙርቴ ፡ ጋር ፡ ፋሲካን ፡ የምበላበት ፡ የእንግዳ ፡ ቤት ፡ ክፍል ፡ ወዴት ፡ ፲፪ ነው ? ይልሃል ፡ በሉት ፤ ያም ፡ በደርብ ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ የተነጠፈ ፡ ታላቅ ፡ አዳራሽ ፡ ያሳያች ፲፫ ኋል ፤ በዚያም ፡ አሰናዱልን ። ሄደውም ፡ እንዳላቸው ፡ አገኙና ፡ ፋሲካን ፡ አሰናዱ ።

፲፬ ሰዓቱም ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ከአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ፲፭ ሐዋርያት ፡ ጋር ፡ በማዕድ ፡ ተቀመጠ ። እርሱም ፦ ከመከራዬ ፡ በፊት ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይህን ፡ ፋሲካ ፡ ልበላ ፡ እጅግ ፡ እመኝ ፡ ነበር ፤ ፲፮ እላችኋለሁና ፥ በእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፥ ወደ ፡ ፊት ፡ ከዚህ ፡ አል ፲፯ በላም ፡ አላቸው ። ጽዋንም ፡ ተቀብሎ ፡ አመስግኖም ፦ ይህን ፡ እንካችሁ ፡ በመካከላችሁም ፡ ተካ ፲፰ ፈሉት ፤ እላችኋለሁና ፥ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ እስክትመጣ ፡ ድረስ ፡ ከአሁን ፡ ጀምሮ ፡ ፲፱ ከወይኑ ፡ ፍሬ ፡ አልጠጣም ፡ አለ ። እንጀራንም ፡ አንሥቶ ፡ አመስግኖ ፡ ቈርሶም ፡ ሰጣቸውና ፦ ስለ ፡ እናንተ ፡ የሚሰጠው ፡ ሥጋዬ ፡ ይህ ፡ ነው ! ፳ ይህን ፡ ለመታሰቢያዬ ፡ አድርጉት ፡ አለ ። እንዲሁም ፡ ከእራት ፡ በኋላ ፡ ጽዋውን ፡ አንሥቶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ ይህ ፡ ጽዋ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ በሚፈሰው ፡ በደሜ ፡ የሚሆን ፡ አዲስ ፡ ኪዳን ፡ ነው ። ፳፩ ነገር ፡ ግን ፡ አሳልፎ ፡ የሚሰጠኝ ፡ እጅ ፡ እነሆ ፡ ፳፪ በማዕድ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ናት ። የሰው ፡ ልጅስ ፡ እንደ ፡ ተወሰነው ፡ ይሄዳል ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አልፎ ፡ ፳፫ ለሚሰጥበት ፡ ለዚያ ፡ ሰው ፡ ወዮለት ። ከእነርሱም ፡ ይህን ፡ ሊያደርግ ፡ ያለው ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ይጠያየቁ ፡ ጀመር ።

፳፬ ደግሞም ፡ ማናቸውም ፡ ታላቅ ፡ ሆኖ ፡ እንዲ ፳፭ ቈጠር ፡ በመካከላቸው ፡ ክርክር ፡ ሆነ ። እንዲህም ፡ አላቸው ፦ የአሕዛብ ፡ ነገሥታት ፡ ይገዙአቸዋል ፥ በላያቸውም ፡ የሚሠለጥኑት ፡ ቸርነት ፡ አድራጊዎች ፡ ይባላሉ ። ፳፮ እናንተ ፡ ግን ፡

፳፩ ። ፳፬ ፤ ዳን· ፰ ፥ ፲፫ ፤ ፲፪ ፥ ፯ ። ፳፭ ፤ ኢሳ· ፲፫ ፥ ፲ ። ፳፯ ፤ ዳን· ፯ ፥ ፲፫ ፤ ማቴ· ፳፮ ፥ ፷፬ ። ፴፫ ፤ ኢሳ· ፶፩ ፥ ፮ ። ፴፬ ፤ ሮሜ· ፲፫ ፥ ፲፫ ። ፴፭ ፤ መክ· ፱ ፥ ፲፪ ። ፴፮ ፤ ማቴ· ፳፭ ፥ ፲፫ ፤ ፩ ዮሐ· ፪ ፥ ፳፰ ። ፴፯ ፤ ዮሐ· ፰ ፥ ፩ ፤ ማቴ· ፳፮ ፥ ፶፭ ።

፳፪ ። ፩ ፡ ፪ ፤ ማቴ· ፳፮ ፥ ፪—፭ ፤ ማር· ፲፬ ፥ ፩ ፡ ፪ ። ፪ ፤ መዝ· ፪ ፥ ፪ ፤ ዮሐ· ፲፩ ፥ ፵፯ ፡ ፶፫ ። ፫—፮ ፤ ማቴ· ፳፮ ፥ ፲፬—፲፮ ፤ ማር· ፲፬ ፥ ፲ ፡ ፲፩ ፤ ዮሐ· ፲፫ ፥ ፪ ፡ ፳፯ ። ፯—፲፫ ፤ ዘፀአ· ፲፪ ፥ ፫ ፡ ፮ ፤ ማቴ· ፳፮ ፥ ፲፯—፲፱ ፤ ማር· ፲፬ ፥ ፲፪—፲፮ ። ፲፫ ፤ ማቴ· ፳፮ ፥ ፳፱ ፤ ማር· ፲፬ ፥ ፳፭ ። ፲፬—፳ ፤ ማቴ· ፳፮ ፥ ፳—፳፱ ፤ ማር· ፲፬ ፥ ፲፯—፳፭ ፤ ፩ ቆሮ· ፲፩ ፥ ፳፫—፳፭ ። ፳ ፤ ዘፀአ· ፳፬ ፥ ፰ ። ፳፩—፳፫ ፤ ማቴ· ፳፮ ፥ ፳፩—፳፭ ፤ ማር· ፲፬ ፥ ፲፰—፳፩ ። ፳፪ ፤ ዮሐ· ፱ ፥ ፶፯ ። ፳፬—፳፯ ፤ ማቴ· ፳ ፥ ፳፭—፳፰ ፤ ማር· ፲ ፥ ፵፪—፵፭ ።

እንዲህ ፡ አትሁኑ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከእናንተ ፡ ታላቅ ፡
የሆነ ፡ በመካከላችሁ ፡ እንደ ፡ ታናሽ ፥ የሚገዛም ፡
፳፯ እንደሚያገለግል ፡ ይሁን ። በማዕድ ፡ የተቀ
መጠ ፡ ወይስ ፡ የሚያገለግል ፡ ማናቸው ፡ ታላቅ ፡
ነው ? የተቀመጠው ፡ አይደለምን ? እኔ ፡ ግን ፡
በመካከላችሁ ፡ እንደሚያገለግል ፡ ነኝ ።

፳፰ ነገር ፡ ግን ፡ እናንተ ፡ በፈተናዎቼ ፡ ከእኔ ፡
፳፱፡፴ ጋር ፡ ጸንታችሁ ፡ የኖራችሁ ፡ ናችሁ ፤ አባቴ ፡
እኔን ፡ እንደ ፡ ሾመኝ ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ በመንግ
ሥቴ ፡ ከማዕዴ ፡ ትበሉና ፡ ትጠጡ ፡ ዘንድ ፥ በእ
ሥራ ፡ ሁለቱም ፡ በእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ስትፈርዱ ፡
በዙፋኖች ፡ ትቀመጡ ፡ ዘንድ ፡ ለመንግሥት ፡
እሾማችኋለሁ ።

፴፩ ጌታም ፡— ስምዖን ፡ ስምዖን ፡ ሆይ ፥ እነሆ ፥
ሰይጣን ፡ እንደ ፡ ስንዴ ፡ ሊያበጥራችሁ ፡ ለመነ ፤
፴፪ እኔ ፡ ግን ፡ እምነትህ ፡ እንዳይጠፋ ፡ ስለ ፡ አንተ ፡
አማለድሁ ፤ አንተም ፡ በተመለስህ ፡ ጊዜ ፡ ወን
፴፫ ድሞችህን ፡ አጽና ፡ አለ ። እርሱም ፡— ጌታ ፡
ሆይ ፥ ወደ ፡ ወኅኒም ፡ ወደ ፡ ሞትም ፡ ከአንተ ፡
ጋር ፡ ለመሄድ ፡ የተዘጋጀሁ ፡ ነኝ ፡ አለው ።
፴፬ እርሱ ፡ ግን ፡— ጴጥሮስ ፡ ሆይ ፥ እልሃለሁ ፥ እን
ዳታውቀኝ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ እስክትክደኝ ፡ ድረስ ፡
ዛሬ ፡ ዶሮ ፡ አይጮኽም ፡ አለው ።

፴፭ ደግሞም ፡— ያለ ፡ ኮረጆና ፡ ያለ ፡ ከረጢት ፡
ያለ ፡ ጫማም ፡ በላክኋችሁ ፡ ጊዜ ፥ አንዳች ፡ ጐደ
ለባችሁን ? አላቸው ። እነርሱም ፡— አንዳች ፡
፴፮ እንኳ ፡ አለ ። እርሱም ፡— አሁን ፡ ግን ፡ ኮረጆ ፡
ያለው ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይውሰድ ፥ ከረጢትም ፡
ያለው ፡ እንዲሁ ፤ የሌለውም ፡ ልብሱን ፡ሽጦ ፡
፴፯ ሰይፍ ፡ ይግዛ ። እላችኋለሁና ፥ ይህ ፡— ከዓመ
ፀኞች ፡ ጋር ፡ ተቈጠረ ፡ ተብሎ ፡ የተጻፈው ፡
በእኔ ፡ ሊፈጸም ፡ ግድ ፡ ነው ፤ አዎን ፥ ስለ ፡ እኔ ፡
የሚሆነው ፡ አሁን ፡ ይፈጸማልና ፡ አላቸው ።
፴፰ እነርሱም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ እነሆ ፥ በዚህ ፡ ሁለት ፡
ሰይፎች ፡ አሉ ፡ አሉት ። እርሱም ፡— ይበቃል ፡
አላቸው ።

፴፱ ወጥቶም ፡ እንደ ፡ ልማዱ ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡
ሄደ ፤ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ደግሞ ፡ ተከተሉት ።
፵ ወደ ፡ ስፍራውም ፡ ደርሶ ፡— ወደ ፡ ፈተና ፡ እን
፵፩ ዳትገቡ ፡ ጸልዩ ፡ አላቸው ። ከእነርሱም ፡ የድ
ንጋይ ፡ ውርወራ ፡ የሚያህል ፡ ራቀ ፥ ተንበርክ
፵፪ ኮም ፡— አባት ፡ ሆይ ፥ ብትፈቅድ ፡ ይህችን ፡
ጽዋ ፡ ከእኔ ፡ ውሰድ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የእኔ ፡ ፈቃድ ፡
አይሁን ፡ የአንተ ፡ እንጂ ፡ እያለ ፡ ይጸልይ ፡ ነበር ።
፵፫ ከሰማይም ፡ መጥቶ ፡ የሚያበረታው ፡ መልአክ ፡
፵፬ ታየው ። በፍርሃትም ፡ ሲጣጣር ፡ አጽንቶ ፡ ይጸ
ልይ ፡ ነበር ፤ ወዙም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እንደሚወ
፵፭ ርድ ፡ እንደ ፡ ደም ፡ ነጠብጣብ ፡ ነበረ ። ከጸሎ

ትም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ መጣና ፡
ከኀዘን ፡ የተነሣ ፡ ተኝተው ፡ ሲያገኛቸው ፡—
፵፮ ስለ ፡ ምን ፡ ትተኛላችሁ ? ወደ ፡ ፈተና ፡ እንዳት
ገቡ ፡ ተነሥታችሁ ፡ ጸልዩ ፡ አላቸው ።

፵፯ ገናም ፡ ሲናገር ፡ እነሆ ፥ ሰዎች ፡ መጡ ፤ ከአ
ሥራ ፡ ሁለቱ ፡ አንዱም ፡ ይሁዳ ፡ የሚባለው ፡
ይቀድማቸው ፡ ነበር ፥ ሊስመውም ፡ ወደ ፡ ኢየ
፵፰ ሱስ ፡ ቀረበ ። ኢየሱስ ፡ ግን ፡— ይሁዳ ፡ ሆይ ፥
በመሳም ፡ የሰውን ፡ ልጅ ፡ አሳልፈህ ፡ ትሰጣለ
፵፱ ህን ? አለው ። በዙሪያውም ፡ የነበሩት ፡ የሚ
ሆነውን ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ በሰይፍ ፡
፶ እንምታቸውን ? አሉት ። ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡
የሊቀ ፡ ካህናቱን ፡ ባርያ ፡ መትቶ ፡ ቀኝ ፡ ጆሮ
፶፩ ውን ፡ ቈረጠው ። ኢየሱስ ፡ ግን ፡ መልሶ ፡—
ይህንስ ፡ ፍቀዱ ፡ አለ ፤ ጆሮውንም ፡ ዳስሶ ፡ ፈወ
፶፪ ሰው ። ኢየሱስም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ስለ መጡበት ፡
ለካህናት ፡ አለቆችና ፡ ለመቅደስ ፡ አዛዦች ፡ ለሽ
ማግሌዎችም ፡— ወንበዴን ፡ እንደምትይዙ ፡
፶፫ ሰይፍና ፡ ጕመድ ፡ ይዛችሁ ፡ ወጣችሁን ? በመ
ቅደስ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ስሆን ፡
እጆቻችሁን ፡ አልዘረጋችሁብኝም ፤ ይህ ፡ ግን ፡
ጊዜያችሁና ፡ የጨለማው ፡ሥልጣን ፡ ነው ፡ አላ
ቸው ።

፶፬ ይዘውም ፡ ወሰዱት ፡ ወደ ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡
ቤትም ፡ አገቡት ፤ ጴጥሮስም ፡ ርቆ ፡ ይከተለው ፡
፶፭ ነበር ። በግቢ ፡ መካከልም ፡ እሳት ፡ አንድደው ፡
በአንድነት ፡ ተቀምጠው ፡ ሳሉ ፡ ጴጥሮስ ፡ በመ
፶፮ ካከላቸው ፡ ተቀመጠ ። በብርሃኑም ፡ በኩል ፡
ተቀምጦ ፡ ሳለ ፡ አንዲት ፡ ገረድ ፡ አየችውና ፡
ትኵር ፡ ብላ ፡— ይህ ፡ ደግሞ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡
፶፯ ነበረ ፡ አለች ። እርሱ ፡ ግን ፡— አንቺ ፡ ሴት ፥
፶፰ አላውቀውም ፡ ብሎ ፡ ካደ ። ከጥቂት ፡ ጊዜም ፡
በኋላ ፡ ሌላው ፡ አይቶት ፡— አንተ ፡ ደግሞ ፡ ከእ
ነርሱ ፡ ወገን ፡ ነህ ፡ አለው ። ጴጥሮስ ፡ ግን ፡—
፶፱ አንተ ፡ ሰው ፥ እኔ ፡ አይደለሁም ፡ አለ ። አንድ ፡
ሰዓትም ፡ የሚያህል ፡ ቆይቶ ፡ ሌላው ፡ አስረ
ግጦ ፡— እርሱ ፡ የገሊላ ፡ ሰው ፡ ነውና ፡ በእው
ነት ፡ ይህ ፡ ደግሞ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፡ አለ ።
፷ ጴጥሮስ ፡ ግን ፡— አንተ ፡ ሰው ፥ የምትለውን ፡
አላውቅም ፡ አለ ። ያን ፡ ጊዜም ፡ ገና ፡ ሲናገር ፡
፷፩ ዶሮ ፡ ጮኸ ። ጌታም ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ጴጥሮስን ፡
ተመለከተው ፤ ጴጥሮስም ፡— ዛሬ ፡ ዶሮ ፡ ሳይ
ጮኽ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ትክደኛለህ ፡ እንዳለው ፡
፷፪ የጌታ ፡ ቃል ፡ ትዝ ፡ አለው ። ጴጥሮስም ፡ ወደ ፡
ውጭ ፡ ወጥቶ ፡ ምርር ፡ ብሎ ፡ አለቀሰ ።

፷፫ ኢየሱስንም ፡ የያዙት ፡ ሰዎች ፡ ይዘብቱበትና ፡
፷፬ ይደበድቡት ፡ ነበር ፤ ሸፍነውም ፡ ፊቱን ፡ ይመ
ቱት ፡ ነበርና ፡— በጥፊ ፡ የመታህ ፡ ማን ፡ ነው ?

፳፪ ። ፳፯ ፡ ዮሐ. ፲፫ ፡ ፲፫—፲፬ ። ፳፱ ፡ ማቴ. ፳፭ ፡ ፴፬ ። ፴ ፡ ማቴ. ፲፱ ፡ ፳፰ ። ፴፪ ፡ ዮሐ. ፲፯ ፡ ፱ ፤ ፲፭ ፤ ፳ ። ፴፫ ፡ ዮሐ. ፲፫ ፡ ፴፯ ። ፴፬ ፡ ማቴ. ፳፮ ፡ ፴፬ ፤ ማር. ፲፬ ፡ ፴ ፤ ዮሐ. ፲፫ ፡ ፴፰ ። ፴፭ ፡ ም. ፲ ፡ ፬ ። ፴፯ ፡ ኢሳ. ፶፫ ፡ ፲፪ ። ፴፱—፵፮ ፡ ማቴ. ፳፮ ፡ ፴፮—፵፮ ፤ ማር. ፲፬ ፡ ፴፪—፵፪ ። ፵፪ ፡ ማቴ. ፮ ፡ ፲፪ ። ፵፯—፶፫ ፡ ማቴ. ፳፮ ፡ ፵፯—፶፮ ፤ ማር. ፲፬ ፡ ፵፫—፶ ፤ ዮሐ. ፲፰ ፡ ፫—፲፩ ። ፶፪ ፡ ዮሐ. ፲፰ ፡ ፳ ። ፶፬ ፡ ማቴ. ፳፮ ፡ ፶፯ ፤ ፶፰ ፤ ማር. ፲፬ ፡ ፶፫ ፤ ፶፬ ። ፶፭—፷፪ ፡ ማቴ. ፳፮ ፡ ፷፱—፸፭ ፤ ማር. ፲፬ ፡ ፷፮—፸፪ ፤ ዮሐ. ፲፰ ፡ ፲፭—፲፰ ፤ ፳፭—፳፯ ። ፷፫ ፡ ፷፬ ፡ ማቴ. ፳፮ ፡ ፷፯ ፤ ፷፰ ፤ ማር. ፲፬ ፡ ፷፭ ፤ ዮሐ. ፲፰ ፡ ፳፪ ፤ ፳፫ ።

ትንቢት ፡ ተናገር ፡ እያሉ ፡ ይጠይቁት ፡ ነበር ። ፷፭ ሌላም ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ እየተሳደቡ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ይናገሩ ፡ ነበር ።

፷፮ በነጋም ፡ ጊዜ ፡ የሕዝቡ ፡ ሽማግሌዎችና ፡ የካህናት ፡ አለቆች ፡ ጻፎችም ፡ ተሰብስበው ፡ ፷፯ ወደ ፡ ሸንጎአቸው ፡ ወሰዱትና ፡ ክርስቶስ ፡ አንተ ፡ ነህን ? ንገረን ፡ አሉት ። እርሱ ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ ብነግራችሁ ፡ አታም ፷፰ ኑም ፤ ብጠይቅም ፡ አትመልሱልኝም ፡ አትፈ ፷፱ ቱኝምም ። ነገር ፡ ግን ፡ ከአሁን ፡ ጀምሮ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ኃይል ፡ ቀኝ ፡ ይቀመ ፸ ጣል ። ሁላቸውም ፦ እንግዲያስ ፡ አንተ ፡ የእግ ዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነህን ? አሉት ። እርሱም ፦ እኔ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እናንተ ፡ ትላላችሁ ፡ አላ ፸፩ ቸው ። እነርሱም ፦ ራሳችን ፡ ከአፉ ፡ ሰምተ ናልና ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ምን ፡ ምስክር ፡ ያስ ፈልገናል ? አሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ ሁሉም ፡ በሞላው ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ ጲላ ፪ ጦስ ፡ ወሰዱትና ፦ ይህ ፡ ሕዝባችንን ፡ ሲያጣ ምም ፡ ለቄሣርም ፡ ግብር ፡ እንዳይሰጥ ፡ ሲከለክል ፡ ደግሞም ፦ እኔ ፡ ክርስቶስ ፡ ንጉሥ ፡ ነኝ ፡ ሲል ፡ ፫ አገኘነው ፡ ብለው ፡ ይከሱት ፡ ጀመር ። ጲላ ጦስም ፦ አንተ ፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ ነህን ? ብሎ ፡ ጠየቀው ። እርሱም ፡ መልሶ ፦ አንተ ፡ አልህ ፡ ፬ አለው ። ጲላጦስም ፡ ለካህናት ፡ አለቆችና ፡ ለሕ ዝቡ ፦ በዚህ ፡ ሰው ፡ አንድ ፡ በደል ፡ ስንኳ ፡ ፭ አላገኘሁበትም ፡ አለ ። እነርሱ ፡ ግን ፡ አጽን ተው ፦ ከገሊላ ፡ ጀምሮ ፡ እስከዚህ ፡ ድረስ ፡ በይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ እያስተማረ ፡ ሕዝቡን ፡ ያውከል ፡ አሉ ።

፮ ጲላጦስ ፡ ግን ፦ ገሊላ ፡ ሲሉ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፦ ፯ የገሊላ ፡ ሰው ፡ ነውን ? ብሎ ፡ ጠየቀ ፤ ከሄሮ ድስም ፡ ግዛት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በወቀ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሄሮድስ ፡ ሰደደው ፤ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ በዚያ ፡ ፰ ጊዜ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ነበረና ። ሄሮድስም ፡ ኢየ ሱስን ፡ በየው ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለው ፤ ስለ ፡ እርሱ ፡ ሰለ ፡ ሰማ ፡ ከብዙ ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ ሊያየው ፡ ይመኝ ፡ ነበርና ፥ ምልክትም ፡ ሲያ ፱ ደርግ ፡ ሊያይ ፡ ተስፋ ፡ ያደርግ ፡ ነበር ። በብዙ ፡ ቃልም ፡ ጠየቀው ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ ፲ አልመለሰለትም ። የካህናት ፡ አለቆችና ፡ ጻፎ ችም ፡ አጽንተው ፡ ሲከሱት ፡ ቆመው ፡ ነበር ። ፲፩ ሄሮድስም ፡ ከሠራዊቱ ፡ ጋር ፡ ናቀው ፡ ዘበተበ ትም ፥ የጌጥ ፡ ልብስም ፡ አልብሶ ፡ ወደ ፡ ጲላ ፲፪ ጦስ ፡ መልሶ ፡ ሰደደው ። ሄሮድስና ፡ ጲላጦስም ፡ በዚያን ፡ ቀን ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ወዳጆች ፡ ሆኑ ፥ ቀድሞ ፡ በመካከላቸው ፡ ጥል ፡ ነበረና ።

፲፫ ጲላጦስም ፥ የካህናትን ፡ አለቆችና ፡ መኳንን ፲፬ ትን ፡ ሕዝቡንም ፡ በአንድነት ፡ ጠርቶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ ሕዝቡን ፡ ያጣምማል ፡ ብላችሁ ፡ ይህን ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አመጣችሁት ፤ እነ ሆም ፥ በፊታችሁ ፡ መርምሬ ፡ ክምትከሱበት ፡ ነገር ፡ አንድ ፡ በደል ፡ ስንኳ ፡ በዚህ ፡ ሰው ፡ አላ ፲፭ ገኘሁበትም ። ሄሮድስም ፡ ደግሞ ፡ ምንም ፡ አላ ገኘም ፤ ወደ ፡ እኛ ፡ መልሶታልና ፤ እነሆም ፥ ለሞት ፡ የሚያደርሰው ፡ ምንም ፡ አላደረገም ፤ ፲፮፲፯ እንግዲያስ ፡ ቀጥቼ ፡ እፈታዋለሁ ። በበዓሉ ፡ አንድ ፡ ይፈታላቸው ፡ ዘንድ ፡ ግድ ፡ ነበረና ።

፲፰ ሁላቸውም ፡ በአንድነት ፦ ይህን ፡ አስወግድ ፥ ፲፱ በርባንንም ፡ ፍታልን ፡ እያሉ ፡ ጮኹ ፤ እርሱም ፡ ሁከትን ፡ በከተማ ፡ አንሥቶ ፡ ሰውን ፡ ስለ ፡ ገደለ ፡ ፳ በወኅኒ ፡ ታስሮ ፡ ነበር ። ጲላጦስም ፡ ኢየሱ ስን ፡ ሊፈታ ፡ ወድዶ ፡ ዳግመኛ ፡ ተናገራቸው ፤ ፳፩ ነገር ፡ ግን ፡ እነርሱ ፦ ስቀለው ፡ ስቀለው ፡ እያሉ ፡ ፳፪ ይጮኹ ፡ ነበር ። ሦስተኛም ፦ ምን ፡ ነው ? ያደ ረገው ፡ ክፋት ፡ ምንድር ፡ ነው ? ለሞት ፡ የሚ ያደርሰው ፡ በደል ፡ አላገኘሁበትም ፤ ስለዚህ ፡ ፳፫ ቀጥቼ ፡ እፈታዋለሁ ፡ አላቸው ። እነርሱ ፡ ግን ፡ እንዲሰቀል ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ አጽንተው ፡ ለመ ኑት ። የእነርሱ ፡ ጩኸትና ፡ የካህናት ፡ አለቆ ፳፬ ችም ፡ ቃል ፡ በረታ ። ጲላጦስም ፡ ልመናቸው ፡ ፳፭ እንዲሆንላቸው ፡ ፈረደበት ። ያንን ፡ የለመኑ ትንም ፥ ስለ ፡ ሁከት ፡ ሰውንም ፡ ስለ ፡ መግደል ፡ በወኅኒ ፡ ታስሮ ፡ የነበረውን ፡ አስፈታላቸው ፥ ኢየሱስን ፡ ግን ፡ ለፈቃዳቸው ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠው ።

፳፮ በወሰዱትም ፡ ጊዜ ፡ ስምዖን ፡ የተባለ ፡ የቀ ሬናን ፡ ሰው ፡ ከገጠር ፡ ሲመጣ ፡ ይዘው ፡ ከኢየ ሱስ ፡ በኋላ ፡ መስቀሉን ፡ እንዲሸከም ፡ ጫኑበት ። ፳፯ ዋይ ፡ ዋይ ፡ ከሚሉና ፡ ሙሾ ፡ ከሚያወጡ ፡ ሴቶ ችና ፡ ከሕዝቡ ፡ እጅግ ፡ ብዙዎች ፡ ተከተሉት ። ፳፰፳፱ ኢየሱስ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ እን ዲህ ፡ አለ ፦ እናንተ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ልጆች ፥ ስለ እኔስ ፡ አታልቅሱልኝ ፤ ዳሩ ፡ ግን ፦ መካና ችና ፡ ያልወለዱ ፡ ማኅፀኖች ፡ ያላጠቡ ፡ ጡቶ ችም ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፡ የሚሉበት ፡ ጊዜ ፡ እነሆ ፡ ይመጣልና ፡ ለራሳችሁና ፡ ለልጆቻችሁ ፡ ፴ አልቅሱ ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ተራራዎችን ፦ በላ ያችን ፡ ውደቁ ፥ ኮረብቶችንም ፦ ሰውሩን ፡ ፴፩ ይሉ ፡ ዘንድ ፡ ይጀምራሉ ፤ በእርጥብ ፡ እንጨት ፡ እንዲህ ፡ የሚያደርጉ ፡ ከሆኑ ፥ በደረቀውስ ፡ እንዴት ፡ ይሆን ?

፴፪ ሌሎችንም ፡ ሁለት ፡ ክፉ ፡ አድራጊዎች ፡ ደግሞ ፡ ፴፫ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይገድሉ ፡ ዘንድ ፡ ወሰዱ ። ቀራ ንዮም ፡ ወደሚባል ፡ ስፍራ ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፥ በዚያ ፡ እርሱን ፡ ክፉ ፡ አድራጊዎቹንም ፡ አን ዱን ፡ በቀኝ ፡ ሁለተኛውንም ፡ በግራ ፡ ሰቀሉ ።

፷፯— ፸፩ ፡ ማቴ. ፳፮ ፥ ፷፫—፷፮ ፤ ማር. ፲፬ ፥ ፷፩—፷፬ ።
፳፫ ። ፩ ፡ ማቴ. ፳፯ ፥ ፪ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፩ ፤ ዮሐ. ፲፰ ፥ ፳፰ ። ፪ ፡ [illegible] ፫ ፡ ማቴ. ፳፯ ፥ ፲፩ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፪ ፤ ዮሐ. ፲፰ ፥ [illegible] ። ፬ ፡ ዮሐ. ፲፰ ፥ ፴፰ ፤ ፲፱ ፥ ፬ ፤ ፮ ። ፯ ፡ [illegible] ። ፰ ፡ [illegible] ። ፲፩ ፡ ዮሐ. ፲፱ ፥ ፩ ። ፲፯—፳፭ ፡ ማቴ. ፳፯ ፥ ፲፭—፳፮ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፮—፲፭ ፤ ዮሐ. ፲፰ ፥ ፴፱ ፤ ፲፱ ፥ ፲፮ ። ፳፮ ፡ ማቴ. ፳፯ ፥ ፴፪ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፳፩ ። ፳፱ ፡ [illegible] ። ፴ ፡ [illegible] ። ፴፪ ፡ ፴፫ ፡ ማቴ. ፳፯ ፥ ፴፰ ፤ ፵፬ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፳፯ ፤ ዮሐ. ፲፱ ፥ ፲፰ ።

፴፬ ኢየሱስም ፡— አባት ፡ ሆይ ፥ የሚያደርጉትን ፡ አያውቁምና ፡ ይቅር ፡ በላቸው ፡ አለ ። ልብሱ ፴፭ ንም ፡ ተከፋፍለው ፡ ዕጣ ፡ ተጣጣሉበት ። ሕዝቡም ፡ ቆመው ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ። መኳንንቱም ፡ ደግሞ ፡— ሌሎችን ፡ አዳነ ፤ እርሱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ የተመረጠው ፡ ክርስቶስ ፡ ከሆነ ፥ ፴፮ ራሱን ፡ ያድን ፡ እያሉ ፡ ያፌዙበት ፡ ነበር ። ጭፍሮችም ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ቀርበው ፡ ሆም ፴፯ ጣጤም ፡ አምጥተው ፡— አንተስ ፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ ከሆንህ ፥ ራስህን ፡ አድን ፡ እያሉ ፡ ይዘ ፴፰ ብቱበት ፡ ነበር ። ይህ ፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ በግሪክና ፡ በሮማይስጥ ፡ በዕብራይስ ጥም ፡ ፊደል ፡ የተጻፈ ፡ ጽሕፈት ፡ ደግሞ ፡ በእ ርሱ ፡ ላይ ፡ ነበረ ።

፴፱ ከተሰቀሉት ፡ ከክፉ ፡ አድራጊዎቹም ፡ አንዱ ፡— አንተስ ፡ ክርስቶስ ፡ አይደለህምን ? ራስህንም ፡ ፵ እኛንም ፡ አድን ፡ ብሎ ፡ ሰደበው ። ሁለተኛው ፡ ግን ፡ መልሶ ፡— አንተ ፡ እንደዚህ ፡ በአንድ ፡ ፍርድ ፡ ሳለህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከቶ ፡ አትፈራውምን ? ፵፩ ስለ ፡ አደረግነውም ፡ የሚገባንን ፡ እንቀበላለንና ፡ በእኛስ ፡ እውነተኛ ፡ ፍርድ ፡ ነው ፤ ይህ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ክፉት ፡ አላደረገም ፡ ብሎ ፡ ገሠጸው ። ፵፪ ኢየሱስንም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ በመንግሥትህ ፡ ፵፫ በመጣህ ፡ ጊዜ ፡ አስበኝ ፡ አለው ። ኢየሱስም ፡— እውነት ፡ እልሃለሁ ፥ ዛሬ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ በገነት ፡ ትሆናለህ ፡ አለው ።

፵፬ ስድስት ፡ ሰዓትም ፡ ያህል ፡ ነበረ ፥ ጨለማም ፡ እስከ ፡ ዘጠኝ ፡ ሰዓት ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሆነ ፥ ፵፭ ፀሐይም ፡ ጨለመ ፥ የቤተ ፡ መቅደስም ፡ መጋ ፵፮ ረጃ ፡ ከመካከሉ ፡ ተቀደደ ። ኢየሱስም ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ጮኾ ፡— አባት ፡ ሆይ ፥ ነፍሴን ፡ በእጅህ ፡ አደራ ፡ እሰጣለሁ ፡ አለ ። ይህንም ፡ ፵፯ ብሎ ፡ ነፍሱን ፡ ሰጠ ። የመቶ ፡ አለቃውም ፡ የሆነውን ፡ ነገር ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡— ይህ ፡ ሰው ፡ በእውነት ፡ ጻድቅ ፡ ነበረ ፡ ብሎ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፵፰ አከበረ ። ይህንም ፡ ለማየት ፡ ተከማችተው ፡ የነበሩ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፥ የሆነውን ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፥ ፵፱ ደረታቸውን ፡ እየደቁ ፡ ተመለሱ ። የሚያውቁቱ ፡ ግን ፡ ሁሉ ፡ ከገሊላ ፡ የተከተሉት ፡ ሴቶችም ፡ ይህን ፡ እያዩ ፡ በሩቅ ፡ ቆመው ፡ ነበር ።

፶ እነሆም ፥ በጎና ፡ ጻድቅ ፡ ሰው ፡ የሸንጎ ፡ አማካሪም ፡ የሆነ ፡ ዮሴፍ ፡ የሚባል ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ፶፩ ይህም ፡ በምክራቸውና ፡ በሥራቸው ፡ አልተባበረም ፡ ነበር ፤ አርማትያስም ፡ ከምትባል ፡ ከአይሁድ ፡ ከተማ ፡ ሆኖ ፡ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ ይጠባበቅ ፡ ነበር ። ፶፪ ይኸውም ፡ ወደ ፡ ጲላጦስ ፡ ቀርቦ ፡ የኢየሱስን ፡ ሥጋ ፡ ለመነው ፤ ፶፫ አውርዶም ፡ በተልባ ፡ እግር ፡ ልብስ ፡ ከፈነው ፥ ማንም ፡ ገና ፡ ባልተቀበረበት ፡ ከዓለትም ፡ በተወቀረ ፡ መቃብር ፡ አኖረው ። ፶፬ የመዘጋጀት ፡ ቀንም ፡ ነበረ ፤ ሰንበትም ፡ ሊጀ ፶፭ ምር ፡ ነበረ ። ከገሊላም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የመጡት ፡ ሴቶች ፡ ተከትለው ፡ መቃብሩን ፡ ሥጋውንም ፡ እንዴት ፡ እንዳኖሩት ፡ አዩ ። ተመል ፶፮ ሰውም ፡ ሽቱና ፡ ቅባት ፡ አዘጋጁ ።

በሰንበትም ፡ እንደ ፡ ትእዛዙ ፡ ዐረፉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ ነገር ፡ ግን ፡ ከሳምንቱ ፡ በመጀመሪያው ፡ ቀን ፡ ያዘጋጁትን ፡ ሽቱ ፡ ይዘው ፡ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ አን ዳንዶቹ ፡ ወደ ፡ መቃብሩ ፡ እጅግ ፡ ማልደው ፡ ፪ መጡ ። ድንጋዩንም ፡ ከመቃብሩ ፡ ተንከባሎ ፡ ፫ አገኙት ፥ ገብተውም ፡ የጌታን ፡ የኢየሱስን ፡ ፬ ሥጋ ፡ አላገኙም ። እነርሱም ፡ በዚህ ፡ ሲያመ ነቱ ፥ እነሆ ፥ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ የሚያንጸባርቅ ፡ ፭ ልብስ ፡ ለብሰው ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ቀረቡ ፤ ፈር ተውም ፡ ፊታቸውን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ አቀርቅ ረው ፡ ሳሉ ፥ እንዲህ ፡ አሉአቸው ፡— ሕያውን ፡ ከሙታን ፡ መካከል ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትፈልጋላችሁ ? ፮፯ ተነሥቶአል ፡ እንጂ ፡ በዚህ ፡ የለም ። የሰው ፡ ልጅ ፡ በኃጢአተኞች ፡ እጅ ፡ አልፎ ፡ ሊሰጥና ፡ ሊሰቀል ፡ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ሊነሣ ፡ ግድ ፡ ነው ፡ እያለ ፡ ገና ፡ በገሊላ ፡ ሳለ ፡ ለእናንተ ፡ እንደ ፡ ፰ ፱ ተናገረ ፡ አስቡ ። ቃሉቹንም ፡ አሰቡ ፥ ከመቃ ብሩም ፡ ተመልሰው ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ለአሥራ ፡ ፲ አንዱና ፡ ለሌሎች ፡ ሁሉ ፡ ነገሩአቸው ። ይህ ንም ፡ ለሐዋርያት ፡ የነገሩአቸው ፡ መግደላዊት ፡ ማርያምና ፡ ዮሐና ፡ የያዕቆብም ፡ እናት ፡ ማር ያም ፡ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ ሌሎች ፡ ፲፩ ሴቶች ፡ ነበሩ ። ይህም ፡ ቃል ፡ ቅዠት ፡ መሰሎ ፲፪ ታያቸውና ፡ አላመኑአቸውም ። ጴጥሮስ ፡ ግን ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ሮጠ ፤ በዚያም ፡ ዝቅ ፡ ብሎ ፡ ሲመለከት ፡ የተልባ ፡ እግር ፡ ልብ ሱን ፡ ብቻ ፡ አየ ፤ በሆነውም ፡ ነገር ፡ እየተደነቀ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ።

፲፫ እነሆም ፥ ከእነርሱ ፡ ሁለቱ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ስድሳ ፡ ምዕራፍ ፡ ያህል ፡ ወደሚ ርቅ ፡ ኤማሁስ ፡ ወደሚባል ፡ መንደር ፡ ይሄዱ ፡ ፲፬ ነበር ፤ ስለዚህም ፡ ስለ ፡ ሆነው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ፲፭ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ይነጋገሩ ፡ ነበር ። ሲነጋገ ሩና ፡ ሲመራመሩም ፥ ኢየሱስ ፡ ራሱ ፡ ቀርቦ ፡ ፲፮ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ይሄድ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እን ፲፯ ዳያውቁት ፡ ዓይናቸው ፡ ተይዞ ፡ ነበር ። እር

፳፫ ። ፴፬ ፤ ማቴ. ፭ ፥ ፵፬ ፤ መዝ. ፳፩ ፥ ፲፰ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፴፭ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፳፬ ፤ ዮሐ. ፲፱ ፥ ፳፫ ፡ ፳፬ ። ፴፭ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፴፱ ፡ ፵፫ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፴፩ ፡ ፴፪ ። ፴፰ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፴፯ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፳፮ ፤ ዮሐ. ፲፱ ፥ ፲፱ ። ፴፱ ፤ ማቴ. ፲፯ ፥ ፳፰ ። ፵፬ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፵፭ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፴፫ ። ፵፭ ፤ ዘፀአ. ፳፮ ፥ ፴፩—፴፫ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፶፩ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፴፰ ። ፵፮ ፤ መዝ. ፴ ፥ ፭ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፶ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፴፯ ፤ ዮሐ. ፲፱ ፥ ፴ ። ፵፯ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፶፬ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፴፱ ። ፵፱ ፤ ምዕ. ፰ ፥ ፪ ። ፶—፶፮ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፶፯—፷፩ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፵፪—፵፯ ፤ ዮሐ. ፲፱ ፥ ፴፰—፵፪ ። ፶፩ ፤ ምዕ. ፪ ፥ ፳፭ ፡ ፴፰ ። ፶፮ ፤ ዘፀአ. ፳ ፥ ፲ ።

፳፬ ። ፩—፲ ፤ ማቴ. ፳፰ ፥ ፩—፰ ፤ ማር. ፲፮ ፥ ፩—፰ ፤ ዮሐ. ፳ ፥ ፩ ። ፮ ፤ ማቴ. ፲፮ ፥ ፳፩ ። ፲ ፤ ምዕ. ፰ ፥ ፪ ፡ ፫ ፤ ማቴ. ፳፯ ፥ ፶፮ ፤ ማር. ፲፭ ፥ ፵ ፡ ፵፩ ። ፲፪ ፤ ዮሐ. ፳ ፥ ፫—፯ ። ፲፯ ፤ ዮሐ. ፳ ፥ ፲፬ ፡ ፳፩ ፥ ፬ ።

ሱም ፡— እየጠወለጋችሁ ፡ ስትሄዱ ፡ እርስ ፡ በር
ሳችሁ ፡ የምትነጋገሩአቸው ፡ እነዚህ ፡ ነገሮች ፡
፲፯ ምንድር ፡ ናቸው ? አላቸው ። ቀለዮጳ ፡ የሚባ
ልም ፡ አንዱ ፡ መልሶ ፡— አንተ ፡ በኢየሩሳሌም ፡
እንግዳ ፡ ሆነህ ፡ ሰብቻህ ፡ ትኖራለህን ? በእነዚህ ፡
ቀኖች ፡ በዚያ ፡ የሆነውን ፡ ነገር ፡ አታውቅምን ?
፲፱ አለው ። እርሱም ፡— ይህ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
አላቸው ። እነርሱም ፡ እንዲህ ፡ አሉት ፡— በእ
ግዚአብሔርና ፡ በሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ በሥ
ራና ፡ በቃል ፡ ብርቱ ፡ ነቢይ ፡ ሰለ ፡ ነበረው ፡ ስለ ፡
፳ ናዝሬቱ ፡ ሰለ ፡ ኢየሱስ ፤ እርሱንም ፡ የካህናት ፡
አለቆችና ፡ መኳንንቶቻችን ፡ ለሞት ፡ ፍርድ ፡
እንዲት ፡ አሳልፈው ፡ እንደ ፡ ሰጡትና ፡ እንደ ፡
፳፩ ሰቀሉት ፡ ነው ። እኛ ፡ ግን ፡ እስራኤልን ፡ እንዲ
ቤዥ ፡ ያለው ፡ እርሱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ተስፋ ፡ አድር
ገን ፡ ነበር ፤ ደግሞም ፡ ከዚህ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ይህ ፡
፳፪ ከሆነ ፡ ዛሬ ፡ ሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ነው ። ደግሞም ፡
ከእኛ ፡ ውስጥ ፡ ማልደው ፡ ከመቃብሩ ፡ ሄንድ ፡
፳፫ የነበሩት ፡ አንዳንድ ፡ ሴቶች ፡ አስገረሙን ፤ ሥጋ
ውንም ፡ ባጡ ፡ ጊዜ ፡— ሕያው ፡ ነው ፡ የሚሉ ፡
የመላእክትን ፡ ራእይ ፡ ደግሞ ፡ አየን ፡ ሲሉ ፡
፳፬ መጥተው ፡ ነበር ። ከእኛም ፡ ጋር ፡ ከነበሩት ፡
ወደ ፡ መቃብር ፡ ሄደው ፡ ሴቶች ፡ እንደ ፡ ተናገ
ሩት ፡ ሆኖ ፡ አገኙት ፤ እርሱን ፡ ግን ፡ አላዩትም ።
፳፭ እርሱም ፡— እናንተ ፡ የማታስተውሉ ፤ ነቢያ
ትም ፡ የተናገሩትን ፡ ሁሉ ፡ ልባችሁ ፡ ከማመን ፡
፳፮ የዘገየ ፤ ክርስቶስ ፡ ይህን ፡ መከራ ፡ ይቀበል ፡
ዘንድና ፡ ወደ ፡ ክብሩ ፡ ይገባ ፡ ዘንድ ፡ ይገባው ፡
፳፯ የለምን ? አላቸው ። ከሙሴና ፡ ከነቢያት ፡
ሁሉ ፡ ጀምሮ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ በመጻሕፍት ፡ ሁሉ ፡
የተጻፈውን ፡ ተረጐመላቸው ።

፳፰ ወደሚሄዱበትም ፡ መንደር ፡ ቀረቡ ፤ እር
፳፱ ሱም ፡ ሩቅ ፡ የሚሄድ ፡ መሰላቸው ። እነ
ርሱም ፡— ከእኛ ፡ ጋር ፡ እደር ፤ ማታ ፡ ቀርቦአልና ፡
ቀኑም ፡ ሊመሽ ፡ ጀምሮአል ፡ ብለው ፡ ግድ ፡
፴ አሉት ፤ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ሊያድር ፡ ገባ ። ከእ
ነርሱም ፡ ጋር ፡ በማዕድ ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፡ እንጀራ
ውን ፡ አንሥቶ ፡ ባረከው ፤ ቈርሶም ፡ ሰጣቸው ፤
፴፩ ዓይናቸውም ፡ ተከፈተ ፤ አወቁትም ፤ እርሱም ፡
፴፪ ከእነርሱ ፡ ተሰወረ ። እርስ ፡ በርሳቸውም ፡—
በመንገድ ፡ ሲናገረን ፡ መጻሕፍትንም ፡ ሲከፍት
ልን ፡ ልባችን ፡ ይቃጠልብን ፡ አልነበረምን ? ተባ
፴፫ ፴፬ ባሉ ። በዚያችም ፡ ሰዓት ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ፤ አሥራ ፡ አንዱና ፡ ከእ
ነርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩትም ፡— ጌታ ፡ በእውነት ፡ ተነ
ሥቶአል ፡ ለስምዖንም ፡ ታይቶአል ፡ እያሉ ፡
፴፭ በአንድነት ፡ ተሰብስበው ፡ አገኙአቸው ። እነ
ርሱም ፡ በመንገድ ፡ የሆነውን ፡ እንጀራውንም ፡
በቈረሰ ፡ ጊዜ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ታወቀላቸው ፡
ተረኩላቸው ።

፴፮ ይህንም ፡ ሲነጋገሩ ፡ ኢየሱስ ፡ ራሱ ፡ በመካ
ከላቸው ፡ ቆሞ ፡— ሰላም ፡ ለእናንተ ፡ ይሁን ፡
፴፯ አላቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ ደንግጡና ፡ ፈሩ ፡ መንፈ
፴፰ ስም ፡ ያዩ ፡ መሰላቸው ። እርሱም ፡— ስለ ፡ ምን ፡
ትደነግጣላችሁ ? ስለ ፡ ምንስ ፡ አሳብ ፡ በልባ
፴፱ ችሁ ፡ ይነሣል ? እኔ ፡ ራሴ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እጆ
ቼንና ፡ እግሮቼን ፡ እዩ ፤ በእኔ ፡ እንደምታዩት ፤
መንፈስ ፡ ሥጋና ፡ አጥንት ፡ የለውምና ፡ እኔን ፡
፵ ዳስሳችሁ ፡ እዩ ፡ አላቸው ። ይህንም ፡ ብሎ ፡
፵፩ እጆቹንና ፡ እግሮቹን ፡ አሳያቸው ። እነርሱም ፡
ከደስታ ፡ የተነሣ ፡ ገና ፡ ስላላመኑ ፡ ሲደነቁ ፡
ሳሉ ፡— በዚህ ፡ እንዳች ፡ የሚበላ ፡ አላችሁን ?
፵፪ አላቸው ። እነርሱም ፡ ከተጠበሰ ፡ ዓሣ ፡ አንድ ፡
፵፫ ቁራጭ ፤ ከማር ፡ ወለላም ፡ ሰጡት ፤ ተቀብሎም ፡
በፊታቸው ፡ በላ ።

፵፬ እርሱም ፡— ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ሳለሁ ፡ በሙሴ ፡
ሕግና ፡ በነቢያት ፡ በመዝሙራትም ፡ ስለ ፡ እኔ ፡
የተጻፈው ፡ ሁሉ ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ፡
ብዬ ፡ የነገርኋችሁ ፡ ቃሌ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አላቸው ።
፵፭ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ መጻሕፍትን ፡ ያስተውሉ ፡
፵፮ ዘንድ ፡ አእምሮአቸውን ፡ ከፈተላቸው ፤ እን
ዲህም ፡ አላቸው ፡— ክርስቶስ ፡ መከራ ፡ ይቀበ
ላል ፡ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ከሙታን ፡ ይነሣል ፤
፵፯ በስሙም ፡ ንስሐና ፡ የኃጢአት ፡ ስርየት ፡ ከኢ
የሩሳሌም ፡ ጀምሮ ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ይሰበካል ፡
፵፰ ተብሎ ፡ እንዲሁ ፡ ተጽፎአል ። እናንተም ፡
፵፱ ለዚህ ፡ ምስክሮች ፡ ናችሁ ። እነሆም ፤ አባቴ ፡
የሰጠውን ፡ ተስፋ ፡ እኔ ፡ እልክላችኋለሁ ፤ እና
ንተ ፡ ግን ፡ ከላይ ፡ ኃይል ፡ እስክትለብሱ ፡ ድረስ ፡
በኢየሩሳሌም ፡ ከተማ ፡ ቆዩ ።

፶ እስከ ፡ ቢታንያም ፡ አወጣቸው ፡ እጆቹንም ፡
፶፩ አንሥቶ ፡ ባረካቸው ። ሲባርካቸውም ፡ ከእነ
፶፪ ርሱ ፡ ተለየ ፡ ወደ ፡ ሰማይም ፡ ዐረገ ። እነርሱም ፤
ሰገዱለትና ፡ በብዙ ፡ ደስታ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
፶፫ ተመለሱ ፤ ዘወትርም ፡ እግዚአብሔርን ፡ እያመ
ሰገኑና ፡ እየባረኩ ፡ በመቅደስ ፡ ኖሩ ።

[illegible]

# የጌታችን ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ወንጌል ፡

# ቅዱስ ፡ ዮሐንስ ፡ እንደ ፡ ጻፈው ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ በመጀመሪያው ፡ ቃል ፡ ነበረ ፥ ቃልም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነበረ ፥ ቃልም ፡ እግዚአብሔር ፡ ነበረ ። ፪ ይህ ፡ በመጀመሪያው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነበረ ። ፫ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ ሆነ ፥ ከሆነውም ፡ አንዳች ፡ ስንኳ ፡ ያለ ፡ እርሱ ፡ አልሆነም ። ፬ በእርሱ ፡ ሕይወት ፡ ነበረች ፥ ሕይወትም ፡ ፭ የሰው ፡ ብርሃን ፡ ነበረች ። ብርሃንም ፡ በጨለማ ፡ ይበራል ፥ ጨለማም ፡ አላሸነፈውም ።

፮ ከእግዚአብሔር ፡ የተላከ ፡ ስሙ ፡ ዮሐንስ ፡ ፯ የሚባል ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ በኩል ፡ እንዲያምኑ ፡ ይህ ፡ ስለ ፡ ብርሃን ፡ ይመ ፰ ሰክር ፡ ዘንድ ፡ ለምስክር ፡ መጣ ። ስለ ፡ ብርሃን ፡ ሊመሰክር ፡ መጣ ፡ እንጂ ፥ እርሱ ፡ ብርሃን ፡ አልነበረም ።

፱ ለሰው ፡ ሁሉ ፡ የሚያበራው ፡ እውነተኛው ፡ ፲ ብርሃን ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ ይመጣ ፡ ነበር ። በዓለም ፡ ነበረ ፥ ዓለሙም ፡ በእርሱ ፡ ሆነ ፥ ዓለሙም ፡ አላ ፲፩ ወቀውም ። የእርሱ ፡ ወደ ፡ ሆነው ፡ መጣ ፥ የገዛ ፡ ፲፪ ወገኖቹም ፡ አልተቀበሉትም ። ለተቀበሉት ፡ ሁሉ ፡ ግን ፥ በስሙ ፡ ለሚያምኑት ፡ ለእነርሱ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ሥል ፲፫ ጣንን ፡ ሰጣቸው ፤ እነርሱም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ተወለዱ ፡ እንጂ ፡ ከደም ፡ ወይም ፡ ከሥጋ ፡ ፈቃድ ፡ ወይም ፡ ከወንድ ፡ ፈቃድ ፡ አልተወለዱም ።

፲፬ ቃልም ፡ ሥጋ ፡ ሆነ ፤ ጸጋንና ፡ እውነትንም ፡ ተመልቶ ፡ በእኛ ፡ አደረ ፥ አንድ ፡ ልጅም ፡ ከአባቱ ፡ ዘንድ ፡ እንዳለው ፡ ክብር ፡ የሆነውን ፡ ክብ ፲፭ ሩን ፡ አየን ። ዮሐንስ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ መሰከረ ፡ እንዲህም ፡ ብሎ ፡ ጮኸ ፡— ከእኔ ፡ በኋላ ፡ የሚመጣው ፡ እርሱ ፡ ከእኔ ፡ በፊት ፡ ነበረና ፡ ከእኔ ፡ ይልቅ ፡ የከበረ ፡ ሆኖአል ፤ ስለ ፡ እርሱ ፡ ያል ፲፮ ሁት ፡ ይህ ፡ ነበረ ። እኛ ፡ ሁላችን ፡ ከሙላቱ ፡ ተቀብለን ፡ በጸጋ ፡ ላይ ፡ ጸጋ ፡ ተሰጥቶናልና ፤ ፲፯ ሕግ ፡ በሙሴ ፡ ተሰጥቶ ፡ ነበርና ፤ ጸጋና ፡ እው ፲፰ ነት ፡ ግን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሆነ ። መቼም ፡ ቢሆን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያየው ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ የለም ፤ በአባቱ ፡ እቅፍ ፡ ያለ ፡ አንድ ፡ ልጁ ፡ እርሱ ፡ ተረከው ።

፲፱ አይሁድም ፡— አንተ ፡ ማን ፡ ነህ ? ብለው ፡ ይጠይቁት ፡ ዘንድ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ካህናትንና ፡ ሌዋውያንን ፡ በላኩበት ፡ ጊዜ ፥ የዮሐንስ ፡ ምስ ፳ ክርነት ፡ ይህ ፡ ነው ። መሰከረም ፡ አልካደምም ፤ እኔ ፡ ክርስቶስ ፡ አይደለሁም ፡ ብሎ ፡ መሰከረ ። ፳፩ እንኪያስ ፡ ማን ፡ ነህ ? ኤልያስ ፡ ነህን ? ብለው ፡ ጠየቁት ። አይደለሁም ፡ አለ ። ነቢዩ ፡ ነህን ? ፳፪ አይደለሁም ፡ ብሎ ፡ መለሰ ። እንኪያስ ፡— ማን ፡ ነህ ? ለላኩን ፡ መልስ ፡ እንድንሰጥ ፤ ስለ ፳፫ ራስህ ፡ ምን ፡ ትላለህ ? አሉት ። እርሱም ፡— ነቢዩ ፡ ኢሳይያስ ፡ እንዳለ ፡— የጌታን ፡ መንገድ ፡ አቅኑ ፡ ብሎ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የሚጮኽ ፡ ሰው ፡ ድምፅ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ አለ ።

፳፬ ፳፭ የተላኩትም ፡ ከፈሪሳውያን ፡ ነበሩና ፡— እንኪያስ ፡ አንተ ፡ ክርስቶስ ፡ ወይም ፡ ኤልያስ ፡ ወይም ፡ ነቢዩ ፡ ካይደለህ ፥ ስለ ፡ ምን ፡ ታጠምቃ ፳፮ ለህ ? ብለው ፡ ጠየቁት ። ዮሐንስ ፡ መለሰ ፡— እኔ ፡ በውኃ ፡ አጠምቃለሁ ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ እናንተ ፡ የማታውቁት ፡ በመካከላችሁ ፡ ቆሞአል ፤ ፳፯ እኔ ፡ የጫማውን ፡ ጠፍር ፡ ልፈታ ፡ የማይገባኝ ፥ ከእኔ ፡ በኋላ ፡ የሚመጣው ፡ ከእኔ ፡ ይልቅ ፡ የሚ ፳፰ ከበር ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አላቸው ። ይህ ፡ ነገር ፡ ዮሐንስ ፡ ያጠምቅበት ፡ በነበረው ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ በቢታንያ ፡ በቤተ ፡ ራበ ፡ ሆነ ።

፳፱ በነገው ፡ ዮሐንስ ፡ ኢየሱስን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ሲመጣ ፡ አይቶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— እነሆ ፡ የዓለምን ፡ ኃጢአት ፡ የሚያስወግድ ፡ የእግዚአብ ፴ ሔር ፡ በግ ። አንድ ፡ ሰው ፡ ከእኔ ፡ በኋላ ፡ ይመጣል ፥ ከእኔም ፡ በፊት ፡ ነበርና ፡ ከእኔ ፡ ይልቅ ፡ የከበረ ፡ ሆኖአል ፡ ብዬ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ያልሁት ፡ ፴፩ ይህ ፡ ነው ። እኔም ፡ አላውቀውም ፡ ነበር ፥ ዳሩ ፡ ግን ፡ ለእስራኤል ፡ ይገለጥ ፡ ዘንድ ፡ ስለዚህ ፡ ፴፪ በውኃ ፡ እያጠመቅሁ ፡ እኔ ፡ መጣሁ ። ዮሐንስም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ መሰከረ ፡— መንፈስ ፡ ከሰማይ ፡ እንደ ፡ ርግብ ፡ ሆኖ ፡ ሲወርድ ፡ አየሁ ፤ ፴፫ በእርሱ ፡ ላይም ፡ ኖረ ። እኔም ፡ አላውቀውም ፡ ነበር ፥ ዳሩ ፡ ግን ፡ በውኃ ፡ አጠምቅ ፡ ዘንድ ፡ የላከኝ ፡ እርሱ ፡— መንፈስ ፡ ሲወርድበትና ፡ ሲኖርበት ፡ የምታየው ፥ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ የሚያ ፴፬ ጠምቅ ፡ እርሱ ፡ ነው ፡ አለኝ ። እኔም ፡ አይቻለሁ ፡ እርሱም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ እንደ

፩ ። ፩ ፤ ምሳ. ፲፮ ፥ ፳፪ ፤ ዘፍ. ፩ ፥ ፩ ። ፫ ፤ መዝ. ፴፫ ፥ ፮ ። ፬ ፤ ምሳ. ፩ ፥ ፳፯ ፤ ፲፩ ፥ ፳፭ ፤ ፰ ፥ ፲፪ ፤ ፱ ፥ ፩ ። ፯ ፤ ሚል. ፫ ፥ ፩ ፤ ማቴ. ፫ ፥ ፩ ። ፱ ፤ ምሳ. ፲፪ ፥ ፵፮ ። ፲፪ ፤ ፩ ዮሐ. ፫ ፥ ፩ ። ፲፬ ፤ ምሳ. ፬ ፥ ፲፮ ፤ ማቴ. ፩ ፥ ፲፰ ፤ ሉቃ. ፩ ፥ ፴፩ ። ፲፭ ፤ ማቴ. ፫ ፥ ፲፩ ። ፲፯ ፤ ዘፀ. ፳፬ ፥ ፲፪ ፤ ሮሜ ፩ ፥ ፳፬ ። ፲፰ ፤ ዘፀ. ፴፫ ፥ ፳ ፤ ማቴ. ፲፩ ፥ ፳፯ ፤ ፩ ዮሐ. ፬ ፥ ፲፪ ። ፳ ፤ ሉቃ. ፫ ፥ ፲፭ ። ፳፩ ፤ ዘዳግ. ፲፰ ፥ ፲፭ ፤ ፲፰ ፤ ሚል. ፬ ፥ ፭ ፤ ማቴ. ፲፩ ፥ ፲፬ ። ፳፫ ፤ ኢሳ. ፵ ፥ ፫ ፤ ማቴ. ፫ ፥ ፫ ። ፳፮ ፤ ማር. ፩ ፥ ፫ ፤ የሐዋ. ፳፫ ፥ ፭ ። ፳፯ ፤ ማቴ. ፫ ፥ ፲ ፤ ማር. ፩ ፥ ፯ ፤ ሉቃ. ፫ ፥ ፫ ። ፳፰ ፤ ፳፯ ፤ ማቴ. ፫ ፥ ፲፩ ፤ ማር. ፩ ፥ ፰ ፤ ፰ ፤ ሉቃ. ፫ ፥ ፲፮ ። ፳፱ ፤ ዘፀ. ፲፪ ፥ ፫ ፤ ኢሳ. ፶፫ ፥ ፯ ፤ ፩ ዮሐ. ፪ ፥ ፪ ። ፴፩ ፤ ሉቃ. ፩ ፥ ፲፯ ፤ ፵፯ ፤ ፸፯ ። ፴፪ ፤ ማቴ. ፫ ፥ ፲፮ ፤ ማር. ፩ ፥ ፲ ፤ ሉቃ. ፫ ፥ ፳፪ ። ፴፫ ፤ ሉቃ. ፫ ፥ ፯ ፤ ፲፮ ፤ ማቴ. ፫ ፥ ፲፮ ፤ ማር. ፩ ፥ ፰ ።

ሆን ፡ መሰከርሁ ።
፴፭ በነገው ፡ ደግሞ ፡ ዮሐንስ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙር
፴፮ ቱም ፡ ሁለት ፡ ቆመው ፡ ነበር ፥ ኢየሱስም ፡ ሲሄድ ፡
ተመልክቶ ፡ — እነሆ ፡ የእግዚአብሔር ፡ በግ ፡
፴፯ አለ ። ሁለቱም ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ሲናገር ፡
፴፰ ሰምተው ፡ ኢየሱስን ፡ ተከተሉት ። ኢየሱስም ፡
ዘወር ፡ ብሎ ፡ ሲከተሉትም ፡ አይቶ ፡ — ምን ፡
፴፱ ትፈልጋላችሁ ? አላቸው ። እነርሱም ፡ — ረቢ ፥
ወዴት ፡ ትኖራለህ ? አሉት ፤ ትርጓሜው ፡
፵ መምህር ፡ ሆይ ፡ ማለት ፡ ነው ። መጥታችሁ ፡
እዩ ፡ አላቸው ። መጥተው ፡ የሚኖርበትን ፡
እዩ ፥ በዚያም ፡ ቀን ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ዋሉ ፤
፵፩ አሥር ፡ ሰዓት ፡ ያህል ፡ ነበረ ። ከዮሐንስ ፡ ዘንድ ፡
ሰምተው ፡ ከተከተሉት ፡ ከሁለቱ ፡ አንዱ ፡ የስ
ምዖን ፡ ጴጥሮስ ፡ ወንድም ፡ እንድርያስ ፡ ነበረ ።
፵፪ እርሱ ፡ አስቀድሞ ፡ የራሱን ፡ ወንድም ፡ ስምዖ
ንን ፡ አገኘውና ፡ — መሢሕን ፡ አግኝተናል ፡
አለው ፤ ትርጓሜውም ፡ ክርስቶስ ፡ ማለት ፡
፵፫ ነው ። ወደ ፡ ኢየሱስም ፡ አመጣው ። ኢየሱ
ስም ፡ ተመልክቶ ፡ — አንተ ፡ የዮና ፡ ልጅ ፡ ስም
ዖን ፡ ነህ ፤ አንተ ፡ ኬፋ ፡ ትባላለህ ፡ አለው ፤
ትርጓሜው ፡ ጴጥሮስ ፡ ማለት ፡ ነው ።
፵፬ በነገው ፡ ኢየሱስ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ ሊወጣ ፡
ወደደ ፥ ፊልጶስንም ፡ አገኘና ፡ — ተከተለኝ ፡
፵፭ አለው ። ፊልጶስም ፡ ከእንድርያስና ፡ ከጴጥሮስ ፡
፵፮ ከተማ ፡ ከቤተ ፡ ሳይዳ ፡ ነበረ ። ፊልጶስ ፡ ናትና
ኤልን ፡ አግኝቶ ፡ — ሙሴ ፡ በሕግ ፡ ነቢያትም ፡
ስለ ፡ እርሱ ፡ የጻፉትን ፡ የዮሴፍን ፡ ልጅ ፡ የናዝ
፵፯ ሬቱን ፡ ኢየሱስን ፡ አግኝተነዋል ፡ አለው ። ናት
ናኤልም ፡ — ከናዝሬት ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ሊወጣ ፡
ይችላልን ? አለው ። ፊልጶስ ፡ — መጥተህ ፡
፵፰ እይ ፡ አለው ። ኢየሱስ ፡ ናትናኤልን ፡ ወደ ፡
እርሱ ፡ ሲመጣ ፡ አይቶ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ — ተን
ኰል ፡ የሌለበት ፡ በእውነት ፡ የእስራኤል ፡ ሰው ፡
፵፱ እነሆ ፡ አለ ። ናትናኤልም ፡ — ከወዴት ፡ ታው
ቀኛለህ ? አለው ። ኢየሱስም ፡ መለሰ ፡ — ፊል
ጶስ ፡ ሳይጠራህ ፥ ከበለስ ፡ በታች ፡ ሳለህ ፥ አየ
፶ ሁህ ፡ አለው ። ናትናኤልም ፡ መለሰ ፡ — መም
ህር ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነህ ፤
አንተ ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ነህ ፡ አለው ።
፶፩ ኢየሱስም ፡ መለሰ ፡ — ከበለስ ፡ በታች ፡ አየ
ሁህ ፡ ስላልሁህ ፡ አመንህን ? ከዚህ ፡ የሚበ
፶፪ ልጥ ፡ ነገር ፡ ታያለህ ፡ አለው ። እውነት ፡ እው
ነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ሰማይ ፡ ሲከፈት ፡ የእግዚአ
ብሔርም ፡ መላእክት ፡ በሰው ፡ ልጅ ፡ ላይ ፡ ሲወ
ጡና ፡ ሲወርዱ ፡ ታያላችሁ ፡ አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ በገሊላ ፡ ቃና ፡ ሰርግ ፡
ነበረ ፥ የኢየሱስም ፡ እናት ፡ በዚያ ፡ ነበረች ፤
፪ ኢየሱስም ፡ ደግሞ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ወደ ፡
፫ ሰርጉ ፡ ታደሙ ። የወይን ፡ ጠጅም ፡ ባለቀ ፡
ጊዜ ፡ የኢየሱስ ፡ እናት ፡ — የወይን ፡ ጠጅ ፡ እኮ ፡
፬ የላቸውም ፡ አለችው ። ኢየሱስም ፡ — አንቺ ፡
ሴት ፥ ከአንቺ ፡ ጋር ፡ ምን ፡ አለኝ ? ጊዜዬ ፡ ገና ፡
፭ አልደረሰም ፡ አላት ። እናቱም ፡ ለአገልጋዮቹ ፡ —
፮ የሚላችሁን ፡ ሁሉ ፡ አድርጉ ፡ አለቻቸው ። አይ
ሁድም ፡ እንደሚያደርጉት ፡ የማንጻት ፡ ልማድ ፡
ስድስት ፡ የድንጋይ ፡ ጋኖች ፡ በዚያ ፡ ተቀም
ጠው ፡ ነበር ፥ እያንዳንዳቸውም ፡ ሁለት ፡ ወይም ፡
፯ ሦስት ፡ እንስራ ፡ ይይዙ ፡ ነበር ። ኢየሱስም ፡ —
ጋኖቹን ፡ ውኃ ፡ ሙሉአቸው ፡ አላቸው ። እስከ ፡
፰ አፋቸውም ፡ ሞሉአቸው ። አሁን ፡ ቀድታችሁ ፡
ለአሳዳሪው ፡ ስጡት ፡ አላቸው ፤ ሰጡትም ።
፱ አሳዳሪውም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ የሆነውን ፡ ውኃ ፡
በቀመሰ ፡ ጊዜ ፡ ከወዴት ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ አላወ
ቀም ፤ ውኃውን ፡ የቀዱት ፡ አገልጋዮች ፡ ግን ፡
ያውቁ ፡ ነበር ፤ አሳዳሪውም ፡ ሙሽራውን ፡
፲ ጠርቶ ፡ — ሰው ፡ ሁሉ ፡ አስቀድሞ ፡ መልካሙን ፡
የወይን ፡ ጠጅ ፡ ያቀርባል ፥ ከሰከሩም ፡ በኋላ ፡
መናኛውን ፤ አንተስ ፡ መልካሙን ፡ የወይን ፡
፲፩ ጠጅ ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ አቆይተሃል ፡ አለው ። ኢየ
ሱስ ፡ ይህን ፡ የምልክቶች ፡ መጀመሪያ ፡ በገሊላ ፡
ቃና ፡ አደረገ ፤ ክብሩንም ፡ ገለጠ ፥ ደቀ ፡ መዛ
ሙርቱም ፡ በእርሱ ፡ አመኑ ።
፲፪ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከእናቱና ፡ ከወንድሞቹ ፡ ከደቀ ፡
መዛሙርቱም ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ቅፍርናሆም ፡ ወረደ ፥
በዚያም ፡ ጥቂት ፡ ቀን ፡ ኖሩ ።
፲፫ የአይሁድ ፡ ፋሲካም ፡ ቀርቦ ፡ ነበር ፥ ኢየሱ
፲፬ ስም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወጣ ። በመቅደስም ፡
በሬዎችንና ፡ በጎችን ፡ ርግቦችንም ፡ የሚሸጡ
ትን ፡ ገንዘብ ፡ ለዋጮችንም ፡ ተቀምጠው ፡ አገኘ ፤
፲፭ የገመድም ፡ ጅራፍ ፡ አበጅቶ ፡ ሁሉን ፡ በጎች
ንም ፡ በሬዎችንም ፡ ከመቅደስ ፡ አወጣቸው ፥
የለዋጮችንም ፡ ገንዘብ ፡ አፈሰሰ ፡ ገበታዎቻቸው
፲፮ ንም ፡ ገለበጠ ፥ ርግብ ፡ ሻጮችንም ፡ — ይህን ፡
ከዚህ ፡ ውሰዱ ፤ የአባቴን ፡ ቤት ፡ የንግድ ፡
፲፯ ቤት ፡ አታድርጉት ፡ አላቸው ። ደቀ ፡ መዛሙር
ቱም ፡ — የቤትህ ፡ ቅናት ፡ ይበላኛል ፡ ተብሎ ፡
፲፰ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ አሰቡ ። ስለዚህ ፡ አይሁድ ፡ መል
ሰው ፡ — ይህን ፡ ስለምታደርግ ፡ ምን ፡ ምልክት ፡
፲፱ ታሳየናለህ ? አሉት ። ኢየሱስም ፡ መለሰ ፡ —
ይህን ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ አፍርሱት ፥ በሦስት ፡

፩። [illegible]

፪። [illegible]

፳ ቀንም ፡ አነሣዋለሁ ፡ አላቸው ። ስለዚህ ፡ አይሁድ ፡— ይህ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ከአርባ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ ይሠራ ፡ ነበር ፥ አንተስ ፡ በሦ
፳፩ ስት ፡ ቀን ፡ ታነሣዋለህን ? አሉት ። እርሱ ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ሰውነቱ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ይል ፡ ነበር ።
፳፪ ስለዚህ ፡ ከሙታን ፡ ከተነሣ ፡ በኋላ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ይህን ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ አሰቡና ፡ መጽሐፍንና ፡ ኢየሱስ ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ አመኑ ።
፳፫ በፋሲካ ፡ በዓልም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ሳለ ፥ ያደረገውን ፡ ምልክት ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡
፳፬ በስሙ ፡ አመኑ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ኢየሱስ ፡ ሰዎችን ፡ ሁሉ ፡ ያውቅ ፡ ነበር ፤ ስለ ፡ ሰውም ፡ ማንም ፡ ሊመሰክር ፡ አያስፈልገውም ፡ ነበርና ፡ አይተማመናቸውም ፡ ነበር ፤ ራሱ ፡ በሰው ፡ ያለውን ፡ ያውቅ ፡ ነበርና ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ከፈሪሳውያንም ፡ ወገን ፡ የአይሁድ ፡ አለቃ ፡ የሆነ ፡ ኒቆዲሞስ ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤
፪ እርሱም ፡ በሌሊት ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡ መጥቶ ፡— መምህር ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ከሆነ ፡ በቀር ፡ አንተ ፡ የምታደርጋቸውን ፡ እነዚህን ፡ ምልክቶች ፡ ሊያደርግ ፡ የሚችል ፡ የለምና ፡ መምህር ፡ ሆነህ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ዘንድ ፡ እንደ ፡
፫ መጣህ ፡ እናውቃለን ፡ አለው ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡— እውነት ፡ እውነት ፡ እልሃለሁ ፥ ሰው ፡ ዳግመኛ ፡ ካልተወለደ ፡ በቀር ፡ የእግዚአብሔርን ፡
፬ መንግሥት ፡ ሊያይ ፡ አይችልም ፡ አለው ። ኒቆዲሞስም ፡— ሰው ፡ ከሸመገለ ፡ በኋላ ፡ እንዴት ፡ ሊወለድ ፡ ይችላል ? ሁለተኛ ፡ ወደ ፡ እናቱ ፡ ማኅፀን ፡ ገብቶ ፡ ይወለድ ፡ ዘንድ ፡ ይችላልን ?
፭ አለው ። ኢየሱስም ፡ መለሰ ፥ እንዲህ ፡ ሲል ፡— እውነት ፡ እውነት ፡ እልሃለሁ ፥ ሰው ፡ ከውኃና ፡ ከመንፈስ ፡ ካልተወለደ ፡ በቀር ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ሊገባ ፡ አይችልም ።
፮ ከሥጋ ፡ የተወለደ ፡ ሥጋ ፡ ነው ፥ ከመንፈስም ፡
፯ የተወለደ ፡ መንፈስ ፡ ነው ። ዳግመኛ ፡ ልትወለዱ ፡ ያስፈልጋችኋል ፡ ስላልሁህ ፡ አታድንቅ ።
፰ ነፋስ ፡ ወደሚወደው ፡ ይነፍሳል ፥ ድምፁንም ፡ ትሰማለህ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ከወዴት ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ ወዴትም ፡ እንዲሄድ ፡ አታውቅም ፤ ከመን
፱ ፈስ ፡ የተወለደ ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ ነው ። ኒቆዲሞስ ፡ መልሶ ፡— ይህ ፡ እንዴት ፡ ሊሆን ፡ ይች
፲ ላል ? አለው ። ኢየሱስም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— አንተ ፡ የእስራኤል ፡ መምህር ፡ ስትሆን ፡
፲፩ ይህን ፡ አታውቅምን ? እውነት ፡ እውነት ፡ እልሃለሁ ፥ የምናውቀውን ፡ እንናገራለን ፡ ያየነውንም ፡ እንመሰክራለን ፥ ምስክራችንንም ፡ አትቀ

በሉትም ። ስለ ፡ ምድራዊ ፡ ነገር ፡ በነገርኋችሁ ፡ ፲፪
ጊዜ ፡ ካላመናችሁ ፥ ስለ ፡ ሰማያዊ ፡ ነገር ፡ብነግ
ራችሁ ፡ እንዴት ፡ ታምናላችሁ ? ከሰማይም ፡ ፲፫
ከወረደው ፡ በቀር ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ የወጣ ፡ ማንም ፡ የለም ፥ እርሱም ፡ በሰማይ ፡ የሚኖረው ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ነው ። ሙሴም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ እባብን ፡ ፲፬፡፲፭
እንደ ፡ ሰቀለ ፡ እንዲሁ ፡ በእርሱ ፡ የሚያምን ፡ ሁሉ ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ እንዲኖረው ፡ እንጂ ፡ እንዳይጠፋ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ይሰቀል ፡ ይገባዋል ።
፲፮ በእርሱ ፡ የሚያምን ፡ ሁሉ ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ እንዲኖረው ፡ እንጂ ፡ እንዳይጠፋ ፡ እግዚአብሔር ፡ አንድያ ፡ ልጁን ፡ እስኪሰጥ ፡ ድረስ ፡
፲፯ ዓለሙን ፡ እንዲሁ ፡ ወዶአልና ። ዓለም ፡ በልጁ ፡ እንዲድን ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ በዓለም ፡ እንዲፈርድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ አልላከውምና ።
፲፰ በእርሱ ፡ በሚያምን ፡ አይፈረድበትም ፤ በማያ ምን ፡ ግን ፡ በአንዱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡
፲፱ ስም ፡ ስላላመነ ፡ አሁን ፡ ተፈርዶበታል ። ብርሃንም ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ ስለ ፡ መጣ ፡ ሰዎችም ፡ ሥራቸው ፡ ክፉ ፡ ነበርና ፡ ከብርሃን ፡ ይልቅ ፡ ጨለማን ፡ ስለ ፡ ወደዱ ፡ ፍርዱ ፡ ይህ ፡ ነው ።
፳ ክፉ ፡ የሚያደርግ ፡ ሁሉ ፡ ብርሃንን ፡ ይጠላልና ፥ ሥራውም ፡ እንዳይገለጥ ፡ ወደ ፡ ብርሃን ፡ አይመ
፳፩ ጣም ፤ እውነትን ፡ የሚያደርግ ፡ ግን ፡ ሥራው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ተደርጎ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይገለጥ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ብርሃን ፡ ይመጣል ።
፳፪ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ኢየሱስ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ አገር ፡ መጣ ፥ በዚያም ፡ ከእ
፳፫ ነርሱ ፡ ጋር ፡ ተቀምጦ ፡ ያጠምቅ ፡ ነበር ። ዮሐንስም ፡ ደግሞ ፡ በሳሌም ፡ አቅራቢያ ፡ በሄኖን ፡ በዚያ ፡ ብዙ ፡ ውኃ ፡ ነበርና ፡ ያጠምቅ ፡ ነበር ፥
፳፬ እየመጡም ፡ ይጠመቁ ፡ ነበር ፤ ዮሐንስ ፡ ገና ፡ ወደ ፡ ወኅኒ ፡ አልተጨመረም ፡ ነበርና ።
፳፭ ስለዚህም ፡ በዮሐንስ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርትና ፡ በአይሁድ ፡ መካከል ፡ ስለ ፡ ማንጻት ፡ ክርክር ፡
፳፮ ሆነ ። ወደ ፡ ዮሐንስም ፡ መጥተው ፡— መምህር ፡ ሆይ ፥ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ የነበረው ፡ አንተም ፡ የመሰከርህለት ፥ እነሆ ፥ እርሱ ፡ ያጠምቃል ፡ ሁሉም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ይመ
፳፯ ጣሉ ፡ አሉት ። ዮሐንስ ፡ መለሰ ፥ እንዲህ ፡ ሲል ፡— ከሰማይ ፡ ካልተሰጠው ፡ ሰው ፡ አንዳች ፡
፳፰ ሊቀበል ፡ አይችልም ። እናንተ ፡— እኔ ፡ ክርስቶስ ፡ አይደለሁም ፥ ነገር ፡ ግን ፡— ከእርሱ ፡ በፊት ፡ ተልኬአለሁ ፡ እንዳልሁ ፡ ራሳችሁ ፡
፳፱ ትመሰክሩልኛላችሁ ። ሙሽራይቱ ፡ ያለችው ፡ እርሱ ፡ ሙሽራ ፡ ነው ፤ ቆሞ ፡ የሚሰማው ፡ ሚዜው ፡ ግን ፡ በሙሽራው ፡ ድምፅ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ። እንግዲህ ፡ ይህ ፡ ደስታዬ ፡ ተፈ

፪ ። [illegible]
፫ ። [illegible]

፴ ጸመ ። እርሱ ፡ ሊልቅ ፡ እኔ ፡ ግን ፡ ላንስ ፡ ያስፈልጋል ።

፴፩ ከላይ ፡ የሚመጣው ፡ ከሁሉ ፡ በላይ ፡ ነው ፤ ከምድር ፡ የሚሆነው ፡ የምድር ፡ ነው ፡ የምድሩንም ፡ ይናገራል ። ከሰማይ ፡ የሚመጣው ፡ ከሁሉ ፡ በላይ ፡ ነው ።
፴፪ ያየውንና ፡ የሰማውንም ፡ ይህን ፡ ይመሰክራል ÷ ምስክሩንም ፡ የሚቀበል ፡ የለም ።
፴፫ ምስክሩን ፡ የተቀበለ ፡ እግዚአብሔር ፡ እውነተኛ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አተመ ።
፴፬ እግዚአብሔር ፡ የላከው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ይናገራልና ፤ እግዚአብሔር ፡ መንፈሱን ፡ ሰፍሮ ፡ አይሰጥምና ።
፴፭ አብ ፡ ልጁን ፡ ይወዳል ፡ ሁሉንም ፡ በእጁ ፡ ሰጥቶታል ።
፴፮ በልጁ ፡ የሚያምን ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ አለው ፤ በልጁ ፡ የማያምን ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ይኖራል ፡ እንጂ ፡ ሕይወትን ፡ አያይም ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ እንግዲህ ፡— ኢየሱስ ፡ ከዮሐንስ ፡ ይልቅ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ያደርጋል ፡ ያጠምቅማል ፡ ማለትን ፡ ፈሪሳውያን ፡ እንደ ፡ ሰሙ ፡ ጌታ ፡ በወቀ ፡
፩—፫ ጊዜ ÷ ይሁዳን ፡ ትቶ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ ደግሞ ፡ ሄደ ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ እንጂ ፡ ኢየሱስ ፡
፪ ራሱ ፡ አላጠመቀም ።
፬ በሰማርያም ፡ ሊያልፍ ፡ ግድ ፡ ሆነበት ።
፭ ስለዚህ ፡ ያዕቆብ ፡ ለልጁ ፡ ለዮሴፍ ፡ ለሰጠው ፡ ለፍራ ፡ አጠገብ ፡ ወደምትሆን ፡ ሲካር ፡ ወደምትባል ፡ የሰማርያ ፡ ከተማ ፡ መጣ ፤
፮ በዚያም ፡ የያዕቆብ ፡ ጕድጓድ ፡ ነበረ ። ኢየሱስም ፡ መንገድ ፡ ከመሄድ ፡ ደክሞ ፡ በጕድጓዱ ፡ አጠገብ ፡ እንዲሁ ፡ ተቀመጠ ፤ ጊዜውም ፡ ስድስት ፡ ሰዓት ፡ ያህል ፡ ነበረ ።
፯ ከሰማርያ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ውኃ ፡ ልትቀዳ ፡ መጣች ። ኢየሱስም ፡— ውኃ ፡ አጠጪኝ ፡
፰ አላት ፤ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ምግብ ፡ ሊገዙ ፡ ወደ ፡
፱ ከተማ ፡ ሄደው ፡ ነበርና ። ስለዚህ ፡ ሳምራዊቱ ፡— አንተ ፡ የይሁዳ ፡ ሰው ፡ ስትሆን ፡ ሳምራዊት ፡ ሴት ፡ ከምሆን ፡ ከእኔ ፡ መጠጥ ፡ እንዴት ፡ ትለምናለህ ? አለችው ፤ አይሁድ ፡ ከሳምራውያን ፡ ጋር ፡ አይተባበሩም ፡ ነበርና ።
፲ ኢየሱስ ፡ መለሰ ፡— የእግዚአብሔርን ፡ ስጦታና ፡— ውኃ ፡ አጠጪኝ ፡ የሚልሽ ፡ ማን ፡ መሆኑንስ ፡ ብታውቂ ÷ አንቺ ፡ ትለምኚው ፡ ነበርሽ ፡ የሕይወትም ፡ ውኃ ፡ ይሰጥሽ ፡ ነበር ፡ አላት ።
፲፩ ሴቲቱ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ መቅጃ ፡ የለህም ፡ ጕድጓዱም ፡ ጥልቅ ፡ ነው ፤ እንግዲህ ፡ የሕይወት ፡ ውኃ ፡
፲፪ ከወዴት ፡ ታገኛለህ ? በእውነት ፡ አንተ ፡ ይህን ፡ ጕድጓድ ፡ ከሰጠን ፡ ከአባታችን ፡ ከያዕቆብ ፡ ትበልጣለህን ? ራሱም ፡ ልጆቹም ፡ ከብቶቹም ፡ ከዚህ ፡ ጠጥተዋል ፡ አለችው ።
፲፫ ኢየሱስም ፡ መለሰ ፡— ከዚህ ፡ ውኃ ፡ የሚጠጣ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ይጠማል ፤
፲፬ እኔ ፡ ከምሰጠው ፡ ውኃ ፡ የሚጠጣ ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ አይጠማም ÷ እኔ ፡ የምሰጠው ፡ ውኃ ፡ በእርሱ ፡ ውስጥ ፡ ለዘላለም ፡ ሕይወት ፡ የሚፈልቅ ፡ የውኃ ፡ ምንጭ ፡ ይሆናል ፡ እንጂ ፡ አላት ።
፲፭ ሴቲቱ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ እንዳልጠማ ፡ ውኃም ፡ ልቀዳ ፡ ወደዚህ ፡ እንዳልመጣ ፡ ይህን ፡ ውኃ ፡ ስጠኝ ፡ አለችው ።
፲፮ ኢየሱስም ፡— ሂጂና ፡ ባልሽን ፡ ጠርተሽ ፡ ወደ ፡
፲፯ ዚህ ፡ ነዪ ፡ አላት ። ሴቲቱ ፡ መለሰ ፡— ባል ፡ የለኝም ፡ አለችው ። ኢየሱስ ፡— ባል ፡ የለኝም ፡
፲፰ በማለትሽ ፡ መልካም ፡ ተናገርሽ ፤ አምስት ፡ ባሎች ፡ ነበሩሽና ÷ አሁን ፡ ከአንቺ ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ ባልሽ ፡ አይደለም ፤ በዚህስ ፡ እውነት ፡ ተናገርሽ ፡ አላት ።
፲፱ ሴቲቱ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ አንተ ፡
፳ ነቢይ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ አያለሁ ። አባቶቻችን ፡ በዚህ ፡ ተራራ ፡ ሰገዱ ፤ እናንተም ፡— ሰው ፡ ሊሰግድበት ፡ የሚገባው ፡ ስፍራ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ነው ፡ ትላላችሁ ፡ አለችው ።
፳፩ ኢየሱስም ፡ እንዲህ ፡ አላት ፡— አንቺ ፡ ሴት ÷ እመኚኝ ÷ በዚህ ፡ ተራራ ፡ ወይም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለአብ ፡ የማትሰግዱበት ፡ ጊዜ ፡ ይመጣል ።
፳፪ እናንተስ ፡ ለማታውቁት ፡ ትሰግዳላችሁ ፤ እኛ ፡ መዳን ፡ ከአይሁድ ፡ ነውና ፡ ለምናውቀው ፡ እንሰግዳለን ።
፳፫ ነገር ፡ ግን ፡ ለእውነት ፡ የሚሰግዱ ፡ ለአብ ፡ በመንፈስና ፡ በእውነት ፡ የሚሰግዱበት ፡ ጊዜ ፡ ይመጣል ፡ አሁንም ፡ ሆኖአል ፤ አብ ፡ ሊሰግዱለት ፡
፳፬ እንደ ፡ እነዚህ ፡ ያሉትን ፡ ይሻልና ፤ እግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ነው ÷ የሚሰግዱለትም ፡ በመንፈስና ፡ በእውነት ፡ ሊሰግዱለት ፡ ያስፈልጋቸዋል ።
፳፭ ሴቲቱ ፡— ክርስቶስ ፡ የሚባል ፡ መሲሕ ፡ እንዲመጣ ፡ አውቃለሁ ፤ እርሱ ፡ ሲመጣ ፡ ሁሉን ፡ ይነግረናል ፡ አለችው ።
፳፮ ኢየሱስ ፡— የምናገርሽ ፡ እኔ ፡ እርሱ ፡ ነኝ ፡ አላት ።
፳፯ በዚያም ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ መጡና ፡ ከሴት ፡ ጋር ፡ በመነጋገሩ ፡ ተደነቁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡— ምን ፡ ትፈልጊያለሽ ? ወይም ፡— ስለ ፡ ምን ፡ ትናገራታለህ ? ያለ ፡ ማንም ፡ አልነበረም ።
፳፰ ሴቲቱም ፡ እንስራዋን ፡ ትታ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ሄደች ፡
፳፱ ለሰዎችም ፡— ያደረግሁትን ፡ ሁሉ ፡ የነገረኝን ፡ ሰው ፡ ኑና ፡ እዩ ፤ እንጃ ፡ እርሱ ፡ ክርስቶስ ፡ ይሆንን ? አለች ።
፴ ከከተማ ፡ ወጥተው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ይመጡ ፡ ነበር ።
፴፩ ይህም ፡ ሲሆን ፡ ሳለ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡— መምህር ፡ ሆይ ÷ ብላ ፡ ብለው ፡ ለመኑት ።
፴፪ እርሱ ፡ ግን ፡— እናንተ ፡ የማታውቁት ፡ የምበላው ፡
፴፫ መብል ፡ ለእኔ ፡ አለኝ ፡ አላቸው ። ስለዚህ ፡ ደቀ ፡

---

፫። ፴፩፤ ም. ፰ ÷ ፳፫ ። ፴፪፤ ቍ. ፲፩ ። ፴፭፤ ም. ፭ ÷ ፳ ፤ ፲ ÷ ፲፯ ፤ ፲፭ ÷ ፱ ፤ ፲ ፤ ፲፯ ÷ ፳፫ ፤ ፳፯ ፤ ማቴ. ፲፩ ÷ ፳፯ ። ፴፮፤ ም. ፫ ÷ ፲፭ ።

፬። ፩፤ ም. ፫ ÷ ፳፪ ፤ ፳፮ ። ፫፤ ም. ፪ ÷ ፲፪ ፤ ፲፫ ፤ ማቴ. ፬ ÷ ፲፪ ። ፭፤ ዘፍጥ. ፴፫ ÷ ፲፱ ፤ ፵፰ ÷ ፳፪ ፤ ኢያ. ፳፬ ÷ ፴፪ ። ፱፤ ሉቃ. ፱ ÷ ፶፪ ፤ ፶፫ ። ፲፤ ም. ፯ ÷ ፴፯ ። ፲፬፤ ም. ፮ ÷ ፴፭ ፤ ፯ ÷ ፴፰ ፤ ፴፱ ። ፲፱፤ ም. ፱ ÷ ፲፯ ። ፳፤ ዘዳግ. ፲፪ ÷ ፭ ፤ ፮ ፤ ዘዳግ. ፲፪ ÷ ፲፩ ፤ ፳፯ ÷ ፲፪ ፤ ፩ ነገሥ. ፰ ÷ ፳፱ ። ፳፩፤ ሚል. ፩ ÷ ፲፩ ። ፳፪፤ ፪ ነገሥ. ፲፯ ÷ ፳፰ – ፵፩ ፤ መዝ. ፻፵፯ ÷ ፲፱ ፤ ፳ ። ፳፬፤ ዘዳግ. ፲፰ ÷ ፲፰ ።

መዘሙርቱ ፡— የሚበላው ፡ አንዳች ፡ ሰው ፡ አምጥቶለት ፡ ይሆንን ? ተባባሉ ። ፴፬ ኢየሱስም ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— የእኔስ ፡ መብል ፡ የላከኝን ፡ ፈቃድ ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ ሥራውንም ፡ አፈጽም ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ፴፭ እናንተ ፡— ገና ፡ አራት ፡ ወር ፡ ቀርቶአል ፡ መከርም ፡ ይመጣል ፡ ትሉ ፡ የለምን ? እነሆ ፡ እላችኋለሁ ፤ ዓይኖቻችሁን ፡ አንሡ ፡ አዝመራውም ፡ አሁን ፡ እንደ ፡ ነጣ ፡ እርሻውን ፡ ተመልከቱ ። ፴፮ የሚያጭድ ፡ ደመወዝን ፡ ይቀበላል ፤ የሚዘራና ፡ የሚያጭድም ፡ አብረው ፡ ደስ ፡ እንዲላቸው ፡ ለዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ፍሬን ፡ ይሰበስባል ። ፴፯ አንዱ ፡ ይዘራል ፡ አንዱም ፡ ያጭዳል ፡ የሚለው ፡ ቃል ፡ በዚህ ፡ እውነት ፡ ሆኖአልና ። ፴፰ እኔም ፡ እናንተ ፡ ያልደከማችሁበትን ፡ ታጭዱ ፡ ዘንድ ፡ ሰደድኋችሁ ፤ ሌሎች ፡ ደከሙ ፡ እናንተም ፡ በድካማቸው ፡ ገባችሁ ።

፴፱ ሴቲቱም ፡— ያደረግሁትን ፡ ሁሉ ፡ ነገረኝ ፡ ብላ ፡ ስለ ፡ መሰከረችው ፡ ቃል ፡ ከዚያች ፡ ከተማ ፡ የሰማርያ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ አመኑበት ። ፵ የሰማርያ ፡ ሰዎችም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ እንዲኖር ፡ ለመኑት ፤ በዚያም ፡ ሁለት ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ ኖረ ። ፵፩ ስለ ፡ ቃሉም ፡ ከፊተኞች ፡ ይልቅ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ አመኑ ፤ ፵፪ ሴቲቱንም ፡— አሁን ፡ የምናምን ፡ ስለ ፡ ቃልሽ ፡ አይደለም ፤ ለኛ ፡ ራሳችን ፡ ሰምተነዋልና ፤ እርሱም ፡ በእውነት ፡ ክርስቶስ ፡ የዓለም ፡ መድኃኒት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እናውቃለን ፡ ይሉአት ፡ ነበር ።

፵፫ ከሁለቱ ፡ ቀኖችም ፡ በኋላ ፡ ከዚያ ፡ ወጥቶ ፡ ፵፬ ወደ ፡ ገሊላ ፡ ሄደ ። ነቢይ ፡ በገዛ ፡ አገሩ ፡ እንዳይከበር ፡ ኢየሱስ ፡ ራሱ ፡ መስክሮአልና ። ፵፭ ወደ ፡ ገሊላም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፤ የገሊላ ፡ ሰዎች ፡ ራሳቸው ፡ ደግሞ ፡ ለበዓል ፡ መጥተው ፡ ነበርና ፡ በበዓል ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፡ ስላዩ ፡ ተቀበሉት ።

፵፮ ኢየሱስም ፡ ውኃውን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ወዳደረገበት ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ ቃና ፡ ዳግመኛ ፡ መጣ ። በቅፍርናሆምም ፡ ልጁ ፡ የታመመበት ፡ ከንጉሥ ፡ ቤት ፡ አንድ ፡ ሹም ፡ ነበረ ። ፵፯ እርሱም ፡ ኢየሱስ ፡ ከይሁዳ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ ሰምቶ ፡ ልጁ ፡ ሊሞት ፡ ስላለው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ሄደ ፡ ወርዶም ፡ እንዲፈውስለት ፡ ለመነው ። ፵፰ ስለዚህም ፡ ኢየሱስ ፡— ምልክትና ፡ ድንቅ ፡ ነገር ፡ ካላያችሁ ፡ ከቶ ፡ አታምኑም ፡ አለው ። ፵፱ ሹሙም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፤ ብላቴናዬ ፡ ሳይሞት ፡ ውረድ ፡ አለው ። ፶ ኢየሱስም ፡— ሂድ ፤ ልጅህ ፡ በሕይወት ፡ አለ ፡ አለው ። ሰውዬውም ፡ ኢየሱስ ፡ የነገረውን ፡ ቃል ፡ አምኖ ፡ ሄደ ። ፶፩ እርሱም ፡ ሲወርድ ፡ ሳለ ፡ ባሮቹ ፡ ተገናኙትና ፡— ብላቴናህ ፡ በሕይወት ፡ አለ ፡ ብለው ፡ ነገሩት ። ፶፪ እርሱም ፡ በጎ ፡ የሆነበትን ፡ ሰዓት ፡ ጠየቃቸው ፤ እነርሱም ፡— ትናንት ፡ በሰባት ፡ ሰዓት ፡ ንዳዱ ፡ ለቀቀው ፡ አሉት ። ፶፫ አባቱም ፡ ኢየሱስ ፡— ልጅህ ፡ በሕያወት ፡ አለ ፡ ባለው ፡ በዚያ ፡ ሰዓት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አወቀ ፤ እርሱም ፡ ከቤተ ፡ ሰዎቹ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ አመነ ። ፶፬ ይህም ፡ ደግሞ ፡ ኢየሱስ ፡ ከይሁዳ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ መጥቶ ፡ ያደረገው ፡ ሁለተኛ ፡ ምልክት ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የአይሁድ ፡ በዓል ፡ ነበረ ፤ ኢየሱስም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወጣ ።

፪ በኢየሩሳሌምም ፡ በበጎች ፡ በር ፡ አጠገብ ፡ በዕብራይስጥ ፡ ቤተ ፡ ሳይዳ ፡ የምትባል ፡ አንዲት ፡ መጠመቂያ ፡ ነበረች ፤ አምስትም ፡ መመላለሻ ፡ ነበረባት ። ፫ በእነዚህ ፡ ውስጥ ፡ የውኃውን ፡ መንቀሳቀስ ፡ እየጠበቁ ፡ በሽተኞችና ፡ ዕውሮች ፡ አንካሶችም ፡ ሰውነታቸውም ፡ የሰለለ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ይተኙ ፡ ነበር ። ፬ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ የጌታ ፡ መልአክ ፡ ወደ ፡ መጠመቂያይቱ ፡ ወርዶ ፡ ውኃውን ፡ ያናውጥ ፡ ነበርና ፤ እንግዲህ ፡ ከውኃው ፡ መናወጥ ፡ በኋላ ፡ በመጀመሪያ ፡ የገባ ፡ ከማናቸው ፡ ከበሽት ፡ ደዌ ፡ ጤናማ ፡ ይሆን ፡ ነበር ። ፭ በዚያም ፡ ከሠላሳ ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ የታመመ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ፮ ኢየሱስ ፡ ይህን ፡ ሰው ፡ ተኝቶ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፤ እስከ ፡ አሁን ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ እንዲሁ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ አውቆ ፡— ልትድን ፡ ትወዳለህን ? አለው ። ፯ ድውዩም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፤ ውኃው ፡ በተናወጠ ፡ ጊዜ ፡ በመጠመቂያይቱ ፡ ውስጥ ፡ የሚያኖረኝ ፡ ሰው ፡ የለኝም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ እኔ ፡ ስመጣ ፡ ሳለሁ ፡ ሌላው ፡ ቀድሞኝ ፡ ይወርዳል ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ። ፰ ኢየሱስ ፡— ተነሣና ፡ አልጋህን ፡ ተሸክመህ ፡ ሂድ ፡ አለው ። ፱ ወዲያውም ፡ ሰውዬው ፡ ዳነ ፡ አልጋውንም ፡ ተሸክሞ ፡ ሄደ ።

፲ ያም ፡ ቀን ፡ ሰንበት ፡ ነበረ ። ስለዚህ ፡ አይሁድ ፡ የተፈወሰውን ፡ ሰው ፡— ሰንበት ፡ ነው ፡ አልጋህንም ፡ ልትሸከም ፡ አልተፈቀደልህም ፡ አሉት ። ፲፩ እርሱ ፡ ግን ፡— ያዳነኝ ፡ ያ ፡ ሰው ፡— አልጋህን ፡ ተሸክመህ ፡ ሂድ ፡ አለኝ ፡ ብሎ ፡ መለሰላቸው ። ፲፪ እነርሱም ፡— አልጋህን ፡ ተሸክመህ ፡ ሂድ ፡ ያለህ ፡ ሰው ፡ ማን ፡ ነው ? ብለው ፡ ጠየቁት ። ፲፫ ዳኑ ፡ ግን ፡ በዚያ ፡ ስፍራ ፡ ሕዝብ ፡ ስለ ፡ ነበሩ ፡ ኢየሱስ ፡ ፈቀቅ ፡ ብሎ ፡ ነበርና ፡ የተፈወሰው ፡ ሰው ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አላወቀም ። ፲፬ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ኢየሱስ ፡ በመቅደስ ፡ አገኘውና ፡— እነሆ ፤ ድነሃል ፤ ከዚህ ፡ የሚብስ ፡ እንዳይደርስብህ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ኃጢአት ፡ አትሥራ ፡ አለው ። ፲፭ ሰውዬው ፡ ሄዶ ፡ ያዳነው ፡ ኢየሱስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለአይሁድ ፡ ነገረ ። ፲፮ ስለዚህም ፡ በሰንበት ፡ ይህን ፡ ስላደረገ ፡ አይሁድ ፡ ኢየሱስን ፡ ያሳድዱት ፡ ነበር ፡ ሊገድሉትም ፡ ይፈልጉ ፡ ነበር ። ፲፯ ኢየሱስ ፡ ግን ፡— አባቴ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ይሠራል ፡ እኔም ፡ ደግሞ ፡

፬ ። ፴፬ ፡ ም· ፮ ፡ ፴፰ ፡ ፲፯ ፡ ፬ ። ፴፭ ፡ ማቴ· ፱ ፡ ፴፯ ። ፴፰ ፡ ማቴ· ፲፫ ፡ ፲፯ ። ፵፬ ፡ ም· ፲ ፡ ፩ ፡ ፱ ። ፵፭ ፡ ም· ፪ ፡ ፳፫ ። ፶፬ ፡ ም· ፪ ፡ ፲፩ ።

፭ ። ፪ ፡ ነሀም· ፫ ፡ ፩ ። ፲ ፡ [illegible]

፲፰ እሠራለሁ ፡ ብሎ ፡ መለሰላቸው ። እንግዲህ ፡ ሰንበትን ፡ ስለ ፡ ሻረ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ደግሞ ፡ ራሱን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ አስተካክሎ ፡— እግዚአብሔር ፡ አባቴ ፡ ነው ፡ ስላለ ፥ ስለዚህ ፡ አይሁድ ፡ ሊገድሉት ፡ አብዝተው ፡ ይፈልጉት ፡ ነበር ።

፲፱ ስለዚህ ፡ ኢየሱስ ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አላቸው ፡— እውነት ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ አብ ፡ ሲያደርግ ፡ ያየውን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ወልድ ፡ ከራሱ ፡ ሊያደርግ ፡ ምንም ፡ አይችልም ፤ ያ ፡ የሚያደርገውን ፡ ሁሉ ፡ ወልድ ፡ ደግሞ ፡ ይህን ፡ እንዲሁ ፡ ያደርጋልና ። ፳ አብ ፡ ወልድን ፡ ይወዳልና ፥ የሚያደርገውንም ፡ ሁሉ ፡ ያሳየዋል ፤ እናንተም ፡ ትደነቁ ፡ ዘንድ ፡ ከዚህ ፡ የሚበልጥ ፡ ሥራ ፡ ያሳየዋል ። ፳፩ አብ ፡ ሙታንን ፡ እንደሚያነሣ ፡ ሕይወትም ፡ እንደሚሰጣቸው ፥ እንዲሁ ፡ ወልድ ፡ ደግሞ ፡ ለሚወዳቸው ፡ ሕይወትን ፡ ይሰጣቸዋል ። ፳፪ ፳፫ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ አብን ፡ እንደሚያከብሩት ፡ ወልድን ፡ ያከብሩት ፡ ዘንድ ፥ ፍርድን ፡ ሁሉ ፡ ለወልድ ፡ ሰጠው ፡ እንጂ ፡ አብ ፡ በአንድ ፡ ሰው ፡ ስንኳ ፡ አይፈርድም ። ወልድን ፡ የማያከብር ፡ የላከውን ፡ አብን ፡ አያከብርም ። ፳፬ እውነት ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ቃሌን ፡ የሚሰማ ፡ የላከኝንም ፡ የሚያምን ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ አለው ፥ ከሞትም ፡ ወደ ፡ ሕይወት ፡ ተሻገረ ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ፍርድ ፡ አይመጣም ።

፳፭ እውነት ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ ሙታን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ልጅ ፡ ድምፅ ፡ የሚሰሙበት ፡ ሰዓት ፡ ይመጣል ፡ እርሱም ፡ አሁን ፡ ነው ፤ የሚሰሙትም ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉ ። ፳፮ አብ ፡ በራሱ ፡ ሕይወት ፡ እንዳለው ፡ እንዲሁ ፡ ደግሞ ፡ ለወልድ ፡ በራሱ ፡ ሕይወት ፡ እንዲኖረው ፡ ሰጥቶታልና ። ፳፯ የሰው ፡ ልጅም ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ይፈርድ ፡ ዘንድ ፡ ሥልጣን ፡ ሰጠው ። ፳፰ ፳፱ በመቃብር ፡ ያሉቱ ፡ ሁሉ ፡ ድምፁን ፡ የሚሰሙበት ፡ ሰዓት ፡ ይመጣል ፤ መልካምም ፡ ያደረጉ ፡ ለሕይወት ፡ ትንሣኤ ፡ ክፉም ፡ ያደረጉ ፡ ለፍርድ ፡ ትንሣኤ ፡ ይወጣሉና ፡ በዚህ ፡ አታድንቁ ።

፴ እኔ ፡ ከራሴ ፡ አንዳች ፡ ላደርግ ፡ አይቻለኝም ፤ እንደ ፡ ሰማሁ ፡ እፈርዳለሁ ፡ ፍርዴም ፡ቅን ፡ ነው ፥ የላከኝን ፡ ፈቃድ ፡ እንጂ ፡ ፈቃዴን ፡ አልሻምና ። ፴፩ እኔ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ ስለ ፡ ራሴ ፡ ብመሰክር ፡ ፴፪ ምስክሬ ፡ እውነት ፡ አይደለም ፤ ስለ ፡ እኔ ፡ የሚመሰክር ፡ ሌላ ፡ ነው ፥ እርሱም ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ የሚመሰክረው ፡ ምስክር ፡ እውነት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፴፫ አውቃለሁ ። እናንተ ፡ ወደ ፡ ዮሐንስ ፡ ልከ ፡ ፴፬ ችኋል ፡ እርሱም ፡ ለእውነት ፡ መስክሯል ። እኔ ፡ ግን ፡ ከሰው ፡ ምስክር ፡ አልቀበልም ፥ እናንተ ፡ እንድትድኑ ፡ ይህን ፡ እላለሁ ፡ እንጂ ። ፴፭ እርሱ ፡ የሚነድና ፡ የሚያበራ ፡ መብራት ፡ ነበረ ፥ እናንተም ፡ጥቂት ፡ ዘመን ፡ በብርሃኑ ፡ ደስ ፡ ሊላችሁ ፡ ወደዳችሁ ። ፴፮ እኔ ፡ ግን ፡ ከዮሐንስ ፡ ምስክር ፡ የሚበልጥ ፡ ምስክር ፡ አለኝ ፤ አብ ፡ ልፈጽመው ፡ የሰጠኝ ፡ ሥራ ፥ ይህ ፡ የማደርገው ፡ ሥራ ፥ አብ ፡ እንደ ፡ ላከኝ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ ይመሰክራልና ። ፴፯ የላከኝ ፡ አብም ፡ እርሱ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ መስክሯል ። ድምፁን ፡ ከቶ ፡ አልሰማችሁም ፥ መልኩንም ፡ ፴፰ አላያችሁም ፤ እርሱም ፡ የላከውን ፡ እናንተ ፡ አታምኑምና ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ የሚኖር ፡ ቃሉ ፡ የላችሁም ። ፴፱ እናንተ ፡ በመጻሕፍት ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ እንዳላችሁ ፡ ይመስላችኋልና ፡ እነርሱን ፡ ትመረምራላችሁ ፤ እነርሱም ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ የሚመሰክሩ ፡ ናቸው ፤ ፵ ነገር ፡ ግን ፡ ሕይወት ፡ እን ዲሆንላችሁ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ልትመጡ ፡ አትወዱም ። ፵፩ ከሰው ፡ ክብርን ፡ አልቀበልም ፤ ፵፪ እናንተን ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍቅር ፡ በራሳችሁ ፡ እንደ ፡ሌላችሁ ፡ አውቃችኋለሁ ። ፵፫ እኔ ፡ በአባቴ ፡ ስም ፡ መጥቻለሁ ፡ አልተቀበላችሁኝምም ፤ ሌላው ፡ በራሱ ፡ ስም ፡ ቢመጣ ፡ እርሱን ፡ ትቀበሉታላችሁ ። ፵፬ እናንተ ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ክብር ፡ የምትቀባበሉ ፡ ከአንዱም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ያለውን ፡ ክብር ፡ የማትፈልጉ ፥ እንዴት ፡ ልታምኑ ፡ ትችላላችሁ ? ፵፭ እኔ ፡ በአብ ፡ ዘንድ ፡ የምከሳችሁ ፡ አይምሰላችሁ ፤ የሚከሳችሁ ፡ አለ ፤ እርሱም ፡ ተስፋ ፡ የምታደርጉት ፡ ሙሴ ፡ ነው ። ፵፮ ሙሴን ፡ ብታምኑት ፡ እኔን ፡ ባመናችሁ ፡ ነበር ፤ እርሱ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ ጽፎአልና ። ፵፯ መጻሕፍትን ፡ ካላመናችሁ ፡ ግን ፡ ቃሌን ፡ እንዴት ፡ ታምናላችሁ ?

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ኢየሱስ ፡ ወደ ፡ ገሊላ ፡ በሕር ፡ ማዶ ፡ ተሻገረ ፤ እርሱም ፡ የጥብርያዶስ ፡ በሕር ፡ ነው ። ፪ በበሽተኞችም ፡ ያደረገውን ፡ ምልክቶች ፡ ስላዩ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ተከተሉት ። ፫ ኢየሱስም ፡ ወደ ፡ ተራራ ፡ ወጣና ፡ በዚያ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ጋር ፡ ተቀመጠ ። ፬ የአይሁድ ፡ በዓ ልም ፡ ፋሲካ ፡ ቀርቦ ፡ ነበር ። ፭ ኢየሱስም ፡ ዓይኖቹን ፡ አንሥቶ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ሲመጣ ፡ አየና ፡ ፊልጶስን ፡— እነዚህ ፡ እንዲበሉ ፡ እንጀራ ፡ ከወዴት ፡ እንገዛለን ? አለው ። ፮ ራሱ ፡ ሊያደርግ ፡ ያለውን ፡ ያውቅ ፡ ነበርና ፡ ሊፈትነው ፡ ይህን ፡ ተናገረ ። ፯ ፊልጶስ ፡— እያንዳንዳቸው ፡ ትንሽ ፡ ትንሽ ፡ እንኳ ፡ እንዲቀበሉ ፡ የሁለት ፡ መቶ ፡ ዲናር ፡ እንጀራ ፡ አይበቃቸውም ፡ ብሎ ፡

፭ ። ፲፰ ዘሌዋ. [illegible] ... ምዕ. [illegible] ... ሉቃ. [illegible] ... ዳን. [illegible] ... ማቴ. [illegible] ...

፮ ። [illegible] ማቴ. [illegible] ማር. [illegible] ሉቃ. [illegible] ምዕ. [illegible] ።

፰ መለሰለት ። ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ አንዱ ፡ የስ ፱ ምዖን ፡ ጴጥሮስ ፡ ወንድም ፡ እንድርያስ — አም ስት ፡ የገብስ ፡ እንጀራና ፡ ሁለት ፡ ዓሣ ፡ የያዘ ፡ ብላቴና ፡ በዚህ ፡ አለ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እነዚህን ፡ ለሚ ያህሉ ፡ ሰዎች ፡ ይህ ፡ ምን ፡ ይሆናል ? አለው ። ፲ ኢየሱስም ፡— ሰዎቹን ፡ እንዲቀመጡ ፡ አድርጉ ፡ አለ ። በዚያም ፡ ስፍራ ፡ ብዙ ፡ ሣር ፡ ነበረ በት ። ወንዶችም ፡ ተቀመጡ ፡ ቍጥራቸውም ፡ ፲፩ አምስት ፡ ሺህ ፡ የሚያህል ፡ ነበር ። ኢየሱስም ፡ እንጀራውን ፡ ያዘ ፥ አመስግኖም ፡ ለደቀ ፡ መዛ ሙርቱ ፡ ሰጠ ፥ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ለተቀመ ጡት ፡ ሰዎች ፡ ሰጡአቸው ፡ እንዲሁም ፡ ከዓ ፲፪ ሣው ፡ በፈለጉት ፡ መጠን ። ከጠገቡም ፡ በኋላ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን — አንድ ፡ ስንኳ ፡ እንዳይ ጠፋ ፡ የቀረፈውን ፡ ቍርስራሽ ፡ አከማቹ ፡ አላ ፲፫ ቸው ። ስለዚህ ፡ አከማቹ ፥ ከበሉትም ፡ ከአም ስቱ ፡ የገብስ ፡ እንጀራ ፡ የተረፈውን ፡ ቍርስራሽ ፡ ፲፬ አሥራ ፡ ሁለት ፡ መሶብ ፡ ሞሉ ። ከዚህ ፡ የተ ነሣ ፡ ሰዎቹ ፡ ኢየሱስ ፡ ያደረገውን ፡ ምልክት ፡ ባዩ ፡ ጊዜ — ይህ ፡ በእውነት ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ የሚመጣው ፡ ነቢይ ፡ ነው ፡ አሉ ።

፲፭ በዚህም ፡ ምክንያት ፡ ኢየሱስ ፡ ያነግሡት ፡ ዘንድ ፡ ሊመጡና ፡ ሊነጥቁት ፡ እንዳላቸው ፡ አውቆ ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ ተራራ ፡ ብቻውን ፡ ፈቀቅ ፡ አለ ።

፲፮ በመሸም ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ወደ ፡ ፲፯ ባሕር ፡ ወረዱ ፥ በታንኳም ፡ ገብተው ፡ በባሕር ፡ ማዶ ፡ ወደ ፡ ቅፍርናሆም ፡ ይመጡ ፡ ነበር ። አሁ ንም ፡ ጨልሞ ፡ ነበር ፤ ኢየሱስም ፡ ገና ፡ ወደ ፡ ፲፰ እነርሱ ፡ አልመጣም ፡ ነበር ፤ ብርቱ ፡ ነፋስም ፡ ፲፱ ስለ ፡ ነፈሰ ፡ ባሕሩ ፡ ተናወጠ ። ሀያ ፡ አምስት ፡ ወይም ፡ ሠላሳ ፡ ምዕራፍ ፡ ከቀዘፉ ፡ በኋላም ፥ ኢየሱስ ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡ እየሄደ ፡ ወደ ፡ ታንኳ ፳ ይቱ ፡ ሲቀርብ ፡ አይተው ፡ ፈሩ ። እርሱ ፡ ግን ፡— ፳፩ እኔ ፡ ነኝ ፤ አትፍሩ ፡ አላቸው ። ስለዚህ ፡ በታ ንኳይቱ ፡ ሊቀበሉት ፡ ወደዱ ፤ ወዲያውም ፡ ታንኳይቱ ፡ ወደሚሄዱበት ፡ ምድር ፡ ደረሰች ።

፳፪ በነገው ፡ በባሕር ፡ ማዶ ፡ ቆመው ፡ የነበሩ ፡ ሕዝቡ ፡ ከአንዲት ፡ ጀልባ ፡ በቀር ፡ በዚያ ፡ ሌላ ፡ ጀልባ ፡ እንዳልነበረች ፥ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ለብቻቸው ፡ እንደ ፡ ሄዱ ፡ እንጂ ፡ ኢየሱስ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ታንኳይቱ ፡ እን ፳፫ ዳልገባ ፡ አዩ ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ ሌሎች ፡ ጀልባዎች ፡ ጌታ ፡ የባረከውን ፡ እንጀራ ፡ ወደ ፡ በሉበት ፡ ፳፬ ስፍራ ፡ አጠገብ ፡ ከጥብርያዶስ ፡ መጡ ። ሕዝ ቡም ፡ ኢየሱስ ፡ ወይም ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ በዚያ ፡ እንዳልነበሩ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፥ ራሳቸው ፡ በጀ ልባዎቹ ፡ ገብተው ፡ ኢየሱስን ፡ እየፈለጉ ፡ ወደ ፡ ቅፍርናሆም ፡ መጡ ።

፳፭ በባሕር ፡ ማዶም ፡ ሲያገኙት ፡— መምህር ፡ ሆይ ፥ ወደዚህ ፡ መቼ ፡ መጣህ ? አሉት ። ኢየ ፳፮ ሱስም ፡ መልሶ ፡— እውነት ፡ እውነት ፡ እላች ኋለሁ ፥ የምትፈልጉኝ ፡ እንጀራን ፡ ስለ ፡ በላ ችሁና ፡ ስለ ፡ ጠገባችሁ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ምል ፳፯ ክቶችን ፡ ስላያችሁ ፡ አይደለም ። ለሚጠፋ ፡ መብል ፡ አትሥሩ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ሕይ ወት ፡ ለሚኖር ፡ መብል ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ለሚሰ ጣችሁ ፡ ሥሩ ፤ እርሱን ፡ እግዚአብሔር ፡ አብ ፡ ፳፰ አትሞታልና ። እንግዲህ ፡— የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ እንድንሠራ ፡ ምን ፡ እናድርግ ? አሉት ። ፳፱ ኢየሱስ ፡ መልሶ ፡— ይህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሥራ ፡ እርሱ ፡ በላከው ፡ እንድታምኑ ፡ ነው ፡ ፴ አላቸው ። እንግዲህ ፡— እንኪያ ፡ አይተን ፡ እን ድናምንህ ፡ አንተ ፡ ምን ፡ ምልክት ፡ ታደርጋ ፴፩ ለህ ? ምንስ ፡ ትሠራለህ ? ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ ከሰ ማይ ፡ እንጀራ ፡ ሰጣቸው ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ አባቶቻችን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ መና ፡ በሉ ፡ አሉት ። ፴፪ ኢየሱስም ፡— እውነት ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ እውነተኛ ፡ እንጀራ ፡ ከሰማይ ፡ የሚሰጣችሁ ፡ አባቴ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከሰማይ ፡ እንጀራ ፡ የሰጣ ፴፫ ችሁ ፡ ሙሴ ፡ አይደለም ፤ የእግዚአብሔር ፡ እን ጀራ ፡ ከሰማይ ፡ የሚወርድ ፡ ለዓለምም ፡ ሕይወ ፴፬ ትን ፡ የሚሰጥ ፡ ነውና ፡ አላቸው ። ስለዚህ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ እንጀራ ፡ ዘወትር ፡ ስጠን ፡ አሉት ።

፴፭ ኢየሱስም ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— የሕይወት ፡ እንጀራ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ ወደ ፡ እኔ ፡ የሚመጣ ፡ ከቶ ፡ አይራብም ፡ በእኔ ፡ የሚያምንም ፡ ሁልጊዜ ፡ ፴፮ ከቶ ፡ አይጠማም ። ነገር ፡ ግን ፡ አይታችሁኝ ፡ ፴፯ እንዳላመናችሁ ፡ አልኋችሁ ። አብ ፡ የሚሰጠኝ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይመጣል ፥ ወደ ፡ እኔም ፡ የሚ መጣውን ፡ ከቶ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አላወጣውም ፤ ፴፰ ፈቃዴን ፡ ለማድረግ ፡ አይደለም ፡ እንጂ ፡ የላ ከኝን ፡ ፈቃድ ፡ ለማድረግ ፡ ከሰማይ ፡ ወርጃለ ፴፱ ሁና ። ከሰጠኝም ፡ ሁሉ ፡ አንድን ፡ ስንኳ ፡ እን ዳላጠፋ ፡ በመጨረሻው ፡ ቀን ፡ እንዳስነሣው ፡ እንጂ ፡ የላከኝ ፡ የአብ ፡ ፈቃድ ፡ ይህ ፡ ነው ። ፵ ልጁንም ፡ አይቶ ፡ በእርሱ ፡ የሚያምን ፡ ሁሉ ፡ የዘላለም ፡ ሕይወትን ፡ እንዲያገኝ ፡ የአባቴ ፡ ፈቃድ ፡ ይህ ፡ ነው ፥ እኔም ፡ በመጨረሻው ፡ ቀን ፡ አስነሣዋለሁ ።

፵፩ እንግዲህ ፡ አይሁድ ፡— ከሰማይ ፡ የወረደ ፡ እንጀራ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ ስላለ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ አንጐራ ጐሩና ፡— አባቱንና ፡ እናቱን ፡ የምናውቃቸው ፡ ይህ ፡ የዮሴፍ ፡ ልጅ ፡ ኢየሱስ ፡ አይደለምን ? እን ግዲህ ፡— ከሰማይ ፡ ወርጃለሁ ፡ እንዴት ፡ ይላል ? ፵፪ አሉ ። ኢየሱስ ፡ መለሰ ፡ አላቸውም ፡— እርስ ፡ ፵፫ በርሳችሁ ፡ አታንጐራጕሩ ። የላከኝ ፡ አብ ፡ ካሳ ፵፬ በው ፡ በቀር ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ሊመጣ ፡ የሚችል ፡ የለም ፥ እኔም ፡ በመጨረሻው ፡ ቀን ፡ አስነሣዋ

፮ ። ፲፱ ፡ ም. ፭ ፥ ፳፭ ። ፲፭ ፡ ም. ፲፬ ፥ ፲፱ — ፲፭ ። ፲፮ — ፳፩ ፡ ማቴ. ፲፬ ፥ ፳፪ — ፴፫ ፤ ማር. ፮ ፥ ፵፭ — ፶፩ ። ፵ ፡ ም. ፬ ፥ ፲፬ ። ፴፩ ፡ ዘፀአ. ፲፮ ፥ ፲፬ ፡ ፲፭ ፤ ነህም. ፱ ፥ ፲፭ ፤ መዝ. ፸፰ ፥ ፳፬ ። ፴፭ ፡ ም. ፬ ፥ ፲፬ ። ፴፮ ፡ ም. ፲፯ ፥ ፮ ፡ ፰ ። ፴፰ ፡ ም. ፬ ፥ ፴፬ ። ፴፱ ፡ ም. ፲፯ ፥ ፲፪ ። ፵ ፡ ም. ፫ ፥ ፲፭ ። ፵፪ ፡ ማቴ. ፲፫ ፥ ፶፭ ፤ ሉቃ. ፫ ፥ ፳፫ ።

፵፭ ለሁ ። ሁሉም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የተማሩ ፡ ይሆ
ናሉ ፡ ተብሎ ፡ በነቢያት ፡ ተጽፎአል ፤ እንግዲህ ፡
ከአብ ፡ የሰማ ፡ የተማረም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡
፵፮ ይመጣል ። አብን ፡ ያየ ፡ ማንም ፡ የለም ፤ ከእ
ግዚአብሔር ፡ ከሆነ ፡ በቀር ፥ እርሱ ፡ አብን ፡ አይ
፵፯ ቶአል ። እውነት ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ፡ በእኔ ፡
፵፰ የሚያምን ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ አለው ። የሕ
፵፱ ይወት ፡ እንጀራ ፡ እኔ ፡ ነኝ ። አባቶቻችሁ ፡ በም
፶ ድረ ፡ በዳ ፡ መና ፡ በሉ ፡ ሞቱም ፤ ሰው ፡ ከእርሱ ፡
በልቶ ፡ እንዳይሞት ፡ ከሰማይ ፡ አሁን ፡ የወረደ ፡
፶፩ እንጀራ ፡ ይህ ፡ ነው ። ከሰማይ ፡ የወረደ ፡ ሕያው ፡
እንጀራ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ ሰው ፡ ከዚህ ፡ እንጀራ ፡
ቢበላ ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ፤ እኔም ፡ ስለ ፡ ዓለም ፡
ሕይወት ፡ የምሰጠው ፡ እንጀራ ፡ ሥጋዬ ፡ ነው ።
፶፪ እንግዲህ ፡ አይሁድ ፦ ይህ ፡ ሰው ፡ ሥጋውን ፡
ልንበላ ፡ ይሰጠን ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ይችላል ?
፶፫ ብለው ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተከራከሩ ። ስለ
ዚህ ፡ ኢየሱስ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ እውነት ፡
እውነት ፡ እላችኋለሁ ፥ የሰውን ፡ ልጅ ፡ ሥጋ ፡
ካልበላችሁ ፡ ደሙንም ፡ ካልጠጣችሁ ፡ በራሳ
፶፬ ችሁ ፡ ሕይወት ፡ የላችሁም ። ሥጋዬን ፡ የሚ
በላ ፡ ደሜንም ፡ የሚጠጣ ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡
አለው ፥ እኔም ፡ በመጨረሻው ፡ ቀን ፡ አስነሣዋ
፶፭ ለሁ ። ሥጋዬ ፡ እውነተኛ ፡ መብል ፡ ደሜም ፡
፶፮ እውነተኛ ፡ መጠጥ ፡ ነውና ። ሥጋዬን ፡ የሚ
በላ ፡ ደሜንም ፡ የሚጠጣ ፡ በእኔ ፡ ይኖራል ፡
፶፯ እኔም ፡ በእርሱ ፡ እኖራለሁ ። ሕያው ፡ አብ ፡
እንደ ፡ ላከኝ ፡ እኔም ፡ ከአብ ፡ የተነሣ ፡ ሕያው ፡
እንደምሆን ፥ እንዲሁ ፡ የሚበላኝ ፡ ደግሞ ፡
፶፰ ከእኔ ፡ የተነሣ ፡ ሕያው ፡ ይሆናል ። ከሰማይ ፡ የወ
ረደ ፡ እንጀራ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ አባቶቻችሁ ፡ መና ፡
በልተው ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡ አይደለም ፤ ይህን ፡
፶፱ እንጀራ ፡ የሚበላ ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ። በቅ
ፍርናሆም ፡ ሲያስተምር ፡ ይህን ፡ በምኵራብ ፡
አለ ።

፷ ከደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ብዙዎች ፡ በሰሙ ፡
ጊዜ ፦ ይህ ፡ የሚያስጨንቅ ፡ ንግግር ፡ ነው ፤
፷፩ ማን ፡ ሊሰማው ፡ ይችላል ? አሉ ። ኢየሱስ ፡
ግን ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ስለዚህ ፡ እንዳንጐራ
ጐሩ ፡ በልቡ ፡ አውቆ ፡ አላቸው ፦ ይህ ፡ ያሰና
፷፪ ክላችኋልን ? እንግዲህ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ አስቀ
ድሞ ፡ ወደ ፡ ነበረበት ፡ ሲወጣ ፡ ብታዩ ፡ እንዴት ፡
፷፫ ይሆናል ? ሕይወትን ፡ የሚሰጥ ፡ መንፈስ ፡ ነው ፤
ሥጋ ፡ ምንም ፡ አይጠቅምም ፤ እኔ ፡ የነገርኋ
ችሁ ፡ ቃል ፡ መንፈስ ፡ ነው ፡ ሕይወትም ፡ ነው ።
፷፬ ነገር ፡ ግን ፡ ከእናንተ ፡ የማያምኑ ፡ አሉ ። ኢየ
ሱስ ፡ የማያምኑት ፡ እነማን ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ አሳ
ልፎ ፡ የሚሰጠውም ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከመ
፷፭ ጀመሪያ ፡ ያውቅ ፡ ነበርና ። ደግሞ ፦ ስለዚህ ፡
አልኋችሁ ፥ ከአብ ፡ የተሰጠው ፡ ካልሆነ ፡ ወደ ፡
እኔ ፡ ሊመጣ ፡ የሚችል ፡ የለም ፡ አለ ።

፷፮ ከዚህም ፡ የተነሣ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ብዙ
ዎች ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ተመለሱ ፤ ወደ ፡ ፊትም ፡ ከእ
፷፯ ርሱ ፡ ጋር ፡ አልሄዱም ። ኢየሱስም ፡ ለአሥራ ፡
ሁለቱ ፦ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ልትሄዱ ፡ ትወዳላች
፷፰ ሁን ? አለ ። ስምዖን ፡ ጴጥሮስ ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥
ወደ ፡ ማን ፡ እንሄዳለን ? አንተ ፡ የዘላለም ፡ ሕይ
፷፱ ወት ፡ ቃል ፡ አለህ ፤ እኛስ ፡ አንተ ፡ ክርስቶስ ፡
የሕያው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡
አምነናል ፡ አውቀናልም ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።
፸ ኢየሱስም ፦ እኔ ፡ እናንተን ፡ አሥራ ፡ ሁለታ
ችሁን ፡ የመረጥኋችሁ ፡ አይደለምን ? ከእናን
ተም ፡ አንዱ ፡ ዲያብሎስ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ መለሰላ
፸፩ ቸው ። ስለ ፡ ስምዖንም ፡ ልጅ ፡ ስለ ፡ አስቆሮቱ ፡
ይሁዳ ፡ ተናገረ ፤ ከአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ አንዱ ፡
የሆነ ፡ እርሱ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡ አለ
ውና ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ኢየሱስ ፡ አይሁድ ፡ ሊገድ
ሉት ፡ ይፈልጉ ፡ ስለ ፡ ነበር ፡ በይሁዳ ፡ ሊመላ
ለስ ፡ አይወድም ፡ ነበርና ፡ በገሊላ ፡ ይመላለስ ፡
፪ ነበር ። የአይሁድም ፡ የዳስ ፡ በዓል ፡ ቀርቦ ፡
፫ ነበር ። እንግዲህ ፡ ወንድሞቹ ፦ ደቀ ፡ መዛሙ
ርትህ ፡ ደግሞ ፡ የምታደርገውን ፡ ሥራ ፡ እንዲ
ያዩ ፡ ከዚህ ፡ ተነሣና ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ሂድ ፤
፬ ራሱ ፡ ሊገለጥ ፡ እየፈለገ ፡ በስውር ፡ የሚሠራ ፡ የለ
ምና ። እነዚህን ፡ ብታደርግ ፡ ራስህን ፡ ለዓለም ፡
፭ ግለጥ ፡ አሉት ። ወንድሞቹ ፡ ስንኳ ፡ አላመኑ
፮ በትም ፡ ነበርና ። ኢየሱስም ፡ እንዲህ ፡ አላ
ቸው ፦ ጊዜዬ ፡ ገና ፡ አልደረሰም ፥ ጊዜያችሁ ፡
፯ ግን ፡ ዘወትር ፡ የተመቸ ፡ ነው ። ዓለም ፡ እናን
ተን ፡ ሊጠላ ፡ አይቻለውም ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ሥራው ፡
ክፉ ፡ መሆኑን ፡ እመሰክርበታለሁና ፡ እኔን ፡
፰ ይጠላኛል ። እናንተ ፡ ወደዚህ ፡ በዓል ፡ ውጡ ፤
እኔስ ፡ ጊዜዬ ፡ ገና ፡ ስላልተፈጸመ ፡ ወደዚህ ፡
፱ በዓል ፡ ገና ፡ አልወጣም ። ይህንም ፡ አላቸውና ፡
በገሊላ ፡ ቀረ ።

፲ ወንድሞቹ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ በዓሉ ፡ ከወጡ ፡ በኋላ ፡
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ በግልጥ ፡ ሳይ
፲፩ ሆን ፡ ተሰውሮ ፡ ወጣ ። አይሁድም ፦ እርሱ ፡
ወዴት ፡ ነው ? እያሉ ፡ በበዓሉ ፡ ይፈልጉት ፡
፲፪ ነበር ። በሕዝብም ፡ መካከል ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ብዙ ፡
ማንጐራጐር ፡ ነበረ ፤ አንዳንዱም ፦ ደግ ፡
ሰው ፡ ነው ፤ ሌሎች ፡ ግን ፦ አይደለም ፥ ሕዝ
፲፫ ቡን ፡ ግን ፡ ያስታል ፡ ይሉ ፡ ነበር ። ዳሩ ፡ ግን ፡
አይሁድን ፡ ስለ ፡ ፈሩ ፡ ማንም ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡
በግልጥ ፡ አይናገርም ፡ ነበር ።
፲፬ አሁንም ፡ በበዓሉ ፡ እኩሌታ ፡ ኢየሱስ ፡ ወደ ፡
፲፭ መቅደስ ፡ ወጥቶ ፡ ያስተምር ፡ ነበር ። አይሁ

፮ ። ፵፭ ፤ ኢሳ· ፶፬ ፥ ፲፫ ፤ ኤር· ፴፩ ፥ ፴፫ ፡ ፴፬ ። ፵፮ ፤ ም· ፩ ፥ ፲፰ ። ፵፱ ፤ ዘኍ· ፲፩ ። ፶፩ ፤ ም· ፲፩ ፥ ፱ ። ፷፪ ፤ ም· ፫ ፥ ፲፫ ። ፷፫ ፤ ም· ፫ ፥ ፮ ። ፷፬ ፤ ም· ፲፫ ፥ ፲፰ ። ፷፰ ፤ ም· ፩ ፥ ፶ ። ፸ ፤ ም· ፲፫ ፥ ፪ ፤ ፳፯ ፤ ሉቃ· ፳ ፥ ፲፫ ።
፯ ። ፪ ፤ ዘሌዋ· ፳፫ ፥ ፴፬ ። ፫ ፤ ማቴ· ፲፪ ፥ ፵፮ ። ፭ ፤ መዝ· ፷፱ ፥ ፰ ፤ ማር· ፫ ፥ ፳፩ ። ፮ ፤ ም· ፪ ፥ ፬ ። ፯ ፤ ም· ፲፭ ፥ ፲፰ ። ፲፪ ፤ ም· ፱ ፥ ፲፮ ። ፲፫ ፤ ም· ፱ ፥ ፳፪ ። ፲፭ ፤ ማቴ· ፲፫ ፥ ፶፬ ።

ድም ፡— ይህ ፡ ሰው ፡ ሳይማር ፡ መጻሕፍትን ፡ እንዴት ፡ ያውቃል ? ብለው ፡ ይደነቁ ፡ ነበር ። ፲፮ ስለዚህ ፡ ኢየሱስ ፡ መለሰ ፡ እንዲህም ፡ አላቸው ፡— ትምህርቴስ ፡ ከላከኝ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከእኔ ፡ አይ ፲፯ ደለም ፤ ፈቃዱን ፡ ሊያደርግ ፡ የሚወድ ፡ ቢኖር ፥ እርሱ ፡ ይህ ፡ ትምህርት ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ እኔ ፡ ከራሴ ፡ የምናገር ፡ ብሆን ፡ ፲፰ ያውቃል ። ከራሱ ፡ የሚናገር ፡ የራሱን ፡ ክብር ፡ ይፈልጋል ፤ የላከውን ፡ ክብር ፡ የሚፈልግ ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ እውነተኛ ፡ ነው ፡ በእርሱም ፡ ዓመፃ ፡ ፲፱ የለበትም ። ሙሴ ፡ ሕግን ፡ አልሰጣችሁምን ? ከእናንተ ፡ ግን ፡ ሕግን ፡ የሚያደርግ ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ የለም ። ልትገድሉኝ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትፈ ፳ ልጋላችሁ ? ሕዝቡ ፡ መለሱና ፡— ጋኔን ፡ አለ ብህ ፤ ማን ፡ ሊገድልህ ፡ ይፈልጋል ? አሉት ። ፳፩ ኢየሱስ ፡ መለሰ ፡ አላቸውም ፡— አንድ ፡ ሥራ ፡ ፳፪ አደረግሁ ፡ ሁላችሁም ፡ ታደንቃላችሁ ። ስለ ዚህ ፡ ሙሴ ፡ መገረዝን ፡ ሰጣችሁ ፤ ከአበዎ ችም ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከሙሴ ፡ አይደለም ፤ በሰን ፳፫ በትም ፡ ሰውን ፡ ትገርዛላችሁ ። የሙሴ ፡ ሕግ ፡ እንዳይሻር ፡ ሰው ፡ በሰንበት ፡ መገረዝን ፡ የሚ ቀበል ፡ ከሆነስ ፡ ሰውን ፡ ሁለንተናውን ፡ በሰን በት ፡ ጤናማ ፡ ስላደረግሁ ፡ ትቈጡኛላችሁን ? ፳፬ ቅን ፡ ፍርድ ፡ ፍረዱ ፡ እንጂ ፡ በመልክ ፡ አትፍ ረዱ ።

፳፭ እንግዲህ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ሰዎች ፡ አንዳን ዶቹ ፡ እንዲህ ፡ አሉ ፡— ሊገድሉት ፡ የሚፈል ፳፮ ጉት ፡ ይህ ፡ አይደለምን ? እነሆም ፥ በግልጥ ፡ ይናገራል ፡ አንዳችም ፡ አይሉትም ። አለቆቹ ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ በእውነት ፡ ክርስቶስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፳፯ በእውነት ፡ አወቁን ? ነገር ፡ ግን ፡ ይህን ፡ ከወዴት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እውቀናል ፤ ክርስቶስ ፡ ሲመጣ ፡ ግን ፡ ከወዴት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ማንም ፡ አያው ፳፰ ቅም ። እንግዲህ ፡ ኢየሱስ ፡ በመቅደስ ፡ ሲያስ ተምር ፡— እኔንም ፡ ታውቁኛላችሁ ፡ ከወዴትም ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታውቃላችሁ ፤ እኔም ፡ በራሴ ፡ አልመጣሁም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ እናንተ ፡ የማታው ፳፱ ቁት ፡ የላከኝ ፡ እውነተኛ ፡ ነው ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ከእ ርሱ ፡ ዘንድ ፡ ነኝ ፡ እርሱም ፡ ልኮኛልና ፡ አው ፴ ቀዋለሁ ፡ ብሎ ፡ ጮኸ ። ስለዚህ ፡ ሊይዙት ፡ ይፈልጉ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ጊዜው ፡ ገና ፡ ስላልደረሰ ፡ ማንም ፡ እጁን ፡ አልጫነበትም ። ፴፩ ከሕዝቡ ፡ ግን ፡ ብዙዎች ፡ አመኑበትና ፡— ክር ስቶስ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ይህ ፡ ከደረጋቸው ፡ ምል ክቶች ፡ ይልቅ ፡ ያደርጋልን ? አሉ ።

፴፪ ፈሪሳውያን ፡ ሕዝቡ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ እንደዚህ ፡ ሲያንጐራጕሩ ፡ ሰሙ ፤ የካህናት ፡ አለቆችም ፡ ፈሪሳውያንም ፡ ሊይዙት ፡ሎሌዎችን ፡ ላኩ ። ፴፫ ኢየሱስም ፡— ገና ፡ ጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እቆያለሁ ፡ ወደ ፡ ላከኝም ፡ እሄዳለሁ ። ፴፬ ትፈልጉኛላችሁ ፡ አታገኙኝምም ፤ እኔም ፡ ወዳ ለሁበት ፡ እናንተ ፡ ልትመጡ ፡ አትችሉም ፡ አለ ። ፴፭ እንግዲህ ፡ አይሁድ ፡— እኛ ፡ እንዳናገኘው ፡ ይህ ፡ ወዴት ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ አለው ? በግሪክ ፡ ሰዎች ፡ መከከል ፡ ተበትነው ፡ ወደሚኖሩት ፡ ሊሄድና ፡ የግሪክን ፡ ሰዎች ፡ ሊያስተምር ፡ አለ ፴፮ ውን ? እርሱ ፡— ትፈልጉኛላችሁ ፡ አታገኙኝ ምም ፡ እኔም ፡ ወዳለሁበት ፡ እናንተ ፡ ልትመጡ ፡ አትችሉም ፡ የሚለው ፡ ይህ ፡ ቃል ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብለው ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተነጋገሩ ።

፴፯ ከበዓሉም ፡ በታላቁ ፡ በኋለኛው ፡ ቀን ፡ ኢየ ሱስ ፡ ቆሞ ፡— ማንም ፡ የተጠማ ፡ ቢኖር ፡ ወደ ፡ ፴፰ እኔ ፡ ይምጣና ፡ ይጠጣ ። በእኔ ፡ የሚያምን ፥ መጽሐፍ ፡ እንዳለ ፥ የሕይወት ፡ ውኃ ፡ ወንዝ ፡ ፴፱ ከሆዱ ፡ ይፈልቃል ፡ ብሎ ፡ ጮኸ ። ይህን ፡ ግን ፡ በእርሱ ፡ የሚያምኑ ፡ ሊቀበሉት ፡ ስላላቸው ፡ ስለ ፡ መንፈስ ፡ ተናገረ ፤ ኢየሱስ ፡ ገና ፡ ስላል ከበረ ፡ መንፈስ ፡ ገና ፡ አልወረደም ፡ ነበርና ።

፵ ስለዚህ ፡ ከሕዝቡ ፡ አያሌ ፡ ሰዎች ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ሲሰሙ ፡— ይህ ፡ በእውነት ፡ ነቢዩ ፡ ነው ፡ ፵፩ አሉ ፤ ሌሎች ፡— ይህ ፡ ክርስቶስ ፡ ነው ፡ አሉ ፤ ሌሎች ፡ ግን ፡— ክርስቶስ ፡ በእውኑ ፡ ከገሊላ ፡ ፵፪ ይመጣልን ? ክርስቶስ ፡ ከዳዊት ፡ ዘር ፡ ዳዊ ትም ፡ ከነበረበት ፡ መንደር ፡ ከቤተ ፡ ልሔም ፡ እን ፵፫ ዲመጣ ፡ መጽሐፍ ፡ አላለምን ? አሉ ። እንግ ዲህ ፡ ከእርሱ ፡ የተነሣ ፡ በሕዝቡ ፡ መከከል ፡ መለ ፵፬ ያየት ፡ ሆነ ፤ ከእነርሱም ፡ አንዳንዶቹ ፡ ሊይ ዙት ፡ ወደዱ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ እጁን ፡ ማንም ፡ አል ጫነበትም ።

፵፭ ሎሌዎቹም ፡ ወደ ፡ ካህናት ፡ አለቆችና ፡ ወደ ፡ ፈሪሳውያን ፡ መጡ ፤ እነዚያም ፡— ያላመጣች ፵፮ ሁት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ነው ? አሉአቸው ። ሎሌ ዎቹ ፡— እንደዚህ ፡ ሰው ፡ ማንም ፡ እንዲሁ ፡ ከቶ ፡ ፵፯ አልተናገረም ፡ ብለው ፡ መለሱ ። እንግዲህ ፡ ፈሪ ፵፰ ሳውያን ፡— እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ሳታችሁን ? ከአለ ቆች ፡ ወይስ ፡ ከፈሪሳውያን ፡ በእርሱ ፡ ያመነ ፡ ፵፱ አለን ? ነገር ፡ ግን ፡ ሕግን ፡ የማያውቀው ፡ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ርጉም ፡ ነው ፡ ብለው ፡ መለሱላቸው ። ፶ ከእነርሱ ፡ አንዱ ፡ በሌሊት ፡ ቀድሞ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ፶፩ መጥቶ ፡ የነበረ ፡ ኒቆዲሞስ ፡— ሕጋችን ፡ አስቀ ድሞ ፡ ከእርሱ ፡ ሳይሰማ ፡ ምንስ ፡ እንዳደረገ ፡ ሳያውቅ ፡ በሰው ፡ ይፈረዳልን ? አላቸው ። ፶፪ እነርሱም ፡ መለሱና ፡— አንተም ፡ ደግሞ ፡ ከገ ሊላ ፡ ነህን ? ነቢይ ፡ ከገሊላ ፡ እንዳይነሣ ፡ መር ምርና ፡ እይ ፡ አሉት ።

፶፫ እያንዳንዱም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ።

፯ ። [illegible]

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ ኢየሱስ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡ ሄደ ። ፪ ማለዳም ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ ደረሰ ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጡ ። ተቀምጦም ፡ ያስተምራቸው ፡ ነበር ። ፫ ጻፎችና ፡ ፈሪሳውያንም ፡ በምንዝር ፡ የተያዘችን ፡ ሴት ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አመጡ ፡ በመካከልም ፡ እርስዋን ፡ አቁመው ፡— ፬ መምህር ፡ ሆይ ÷ ይህች ፡ ሴት ፡ ስታመነዝር ፡ ተገኝታ ፡ ተያዘች ። ፭ ሙሴም ፡ እንደነዚህ ፡ ያሉት ፡ እንዲወገሩ ፡ በሕግ ፡ አዘዘን ፤ አንተስ ፡ ስለ ፡ እርስዋ ፡ ምን ፡ ትላለህ ? አሉት ። ፮ የሚከሱበትንም ፡ እንዲያገኙ ፡ ሊፈትኑት ፡ ይህን ፡ አሉ ። ኢየሱስ ፡ ግን ፡ ጐንበስ ፡ ብሎ ፡ በጣቱ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ጻፈ ፤ ፯ መላልሰው ፡ በጠየቁት ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ቀና ፡ ብሎ ፡— ከእናንተ ፡ ኃጢአት ፡ የሌለበት ፡ አስቀድሞ ፡ በድንጋይ ፡ ይውገራት ፡ ፰ አላቸው ። ደግሞም ፡ ጐንበስ ፡ ብሎ ፡ በጣቱ ፡ ፱ በምድር ፡ ላይ ፡ ጻፈ ። እነርሱም ፡ ይህን ፡ ሲሰሙ ፡ ሕሊናቸው ፡ ወቀሳቸውና ፡ ከሽማግሌዎች ፡ ጀምረው ፡ እስከ ፡ ኋለኞች ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ እያሉ ፡ ወጡ ፤ ኢየሱስም ፡ ብቻውን ፡ ተረ ፡ ሴቲቱም ፡ ፲ በመካከል ፡ ቆማ ፡ ነበረች ። ኢየሱስም ፡ ቀና ፡ ብሎ ፡ ከሴቲቱ ፡ በቀር ፡ ማንንም ፡ ባላየ ፡ ጊዜ ፡— አንቺ ፡ ሴት ፥ እነዚያ ፡ ከሳሾችሽ ፡ ወዴት ፡ አሉ ? ፲፩ የፈረደብሽ ፡ የለምን ? አላት ። እርስዋም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ አንድ ፡ ስንኳ ፡ አለች ። ኢየሱስም ፡— እኔም ፡ አልፈርድብሽም ፤ ሂጂ ፡ ከአሁንም ፡ ጀምሮ ፡ ደግመሽ ፡ ኃጢአት ፡ አትሥሪ ፡ አላት ።

፲፪ ደግሞም ፡ ኢየሱስ ፡— እኔ ፡ የዓለም ፡ ብርሃን ፡ ነኝ ፤ የሚከተለኝ ፡ የሕይወት ፡ ብርሃን ፡ ይሆንለታል ፡ እንጂ ፡ በጨለማ ፡ አይመላለስም ፡ ብሎ ፡ ፲፫ ተናገራቸው ። ፈሪሳውያንም ፡— አንተ ፡ ስለ ፡ ራስህ ፡ ትመሰክራለህ ፤ ምስክርነትህ ፡ እውነት ፡ ፲፬ አይደለም ፡ አሉት ። ኢየሱስ ፡ መለሰ ፡ አላቸውም ፡— እኔ ፡ ስለ ፡ ራሴ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ብመሰክር ፡ ከወዴት ፡ እንደ ፡ መጣሁ ፡ ወዴትም ፡ እንድሄድ ፡ አውቃለሁና ፡ ምስክርነቴ ፡ እውነት ፡ ነው ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ከወዴት ፡ እንደ ፡ መጣሁ ፡ ፲፭ ወዴትም ፡ እንድሄድ ፡ አታውቁም ። እናንተ ፡ ሥጋዊ ፡ ፍርድን ፡ ትፈርዳላችሁ ፤ እኔ ፡ በአ ፲፮ ንድ ፡ ሰው ፡ በንኳ ፡ አልፈርድም ። የላከኝ ፡ አብ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ብቻዬን ፡ አይደለሁምና ፡ እኔ ፡ ብፈርድ ፡ ፍርዴ ፡ እውነት ፡ ነው ። ፲፯ የሁለት ፡ ሰዎችም ፡ ምስክርነት ፡ እውነት ፡ እንደ ፲፰ ሆነ ፡ በሕጋችሁ ፡ ተጽፎአል ። ስለ ፡ ራሴ ፡ የምመሰክር ፡ እኔ ፡ ነኝ ÷ የላከኝም ፡ አብ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ ፲፱ ይመሰክራል ። እንግዲህ ፡— አባትህ ፡ ወዴት ፡ ነው ? አሉት ። ኢየሱስ ፡ መለሰ ፡— እኔንም ፡ ወይም ፡ አባቴንም ፡ አታውቁም ፤ እኔንስ ፡ ብታውቁኝ ፡ አባቴን ፡ ደግሞ ፡ ባወቃችሁ ፡ ነበር ፡ አላቸው ። ፳ ኢየሱስ ፡ በመቅደስ ፡ ሲያስተምር ፡ በግምጃ ፡ ቤት ፡ አጠገብ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ተናገረ ፤ ጊዜው ፡ ገና ፡ አልደረሰምና ፡ ማንም ፡ አልያዘውም ።

፳፩ ኢየሱስም ፡ ደግሞ ፡— እኔ ፡ እሄዳለሁ ፡ ትፈልጉኛላችሁም ፡ በኃጢአታችሁም ፡ ትሞታላችሁ ፡ እኔ ፡ ወደምሄድበት ፡ እናንተ ፡ ልትመጡ ፡ አትችሉም ፡ አላቸው ። ፳፪ አይሁድም ፡— እኔ ፡ ወደ ምሄድበት ፡ እናንተ ፡ ልትመጡ ፡ አትችሉም ፡ ማለቱ ፡ ራሱን ፡ ይገድላልን ? አንጃ ፡ አሉ ። ፳፫ እናንተ ፡ ከታች ፡ ናችሁ ÷ እኔ ፡ ከላይ ፡ ነኝ ፤ እናንተ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ናችሁ ÷ እኔ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ አይደለሁም ። ፳፬ እንግዲህ ፡— በኃጢአታችሁ ፡ ትሞታላችሁ ፡ አልኋችሁ ፤ እኔ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ባታምኑ ፡ በኃጢአታችሁ ፡ ትሞታላችሁና ፡ አላቸው ። ፳፭ እንግዲህ ፡— አንተ ፡ ማን ፡ ነህ ? አሉት ። ኢየሱስም ፡— ከመጀመሪያ ፡ ለእናንተ ፡ የተናገርሁት ፡ ነኝ ። ፳፮ ስለ ፡ እናንተ ፡ የምናገረው ፡ የምፈርደውም ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ አለኝ ፤ዳሩ ፡ ግን ፡ የላከኝ ፡ እውነተኛ ፡ ነው ፡ እኔም ፡ ከእርሱ ፡ የሰማሁትን ፡ ይህን ፡ ለዓለም ፡ እናገራለሁ ፡ አላቸው ። ፳፯ ስለ ፡ አብ ፡ እንደ ፡ ነገራቸው ፡ ፳፰ አላስተዋሉም ። ስለዚህም ፡ ኢየሱስ ፡— የሰውን ፡ ልጅ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ባደረጋችሁት ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ አባቴም ፡ እንዳስተማረኝ ፡ እንዚህን ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ እንጂ ፡ ከራሴ ፡ አንዳች ፡ እንዳላደርግ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ታውቃላችሁ ። ፳፱ የላከኝም ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ነው ፤ እኔ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡ ዘወትር ፡ አደርጋለሁና ፡ አብ ፡ ብቻዬን ፡ አይተወኝም ፡ አላቸው ። ፴ ይህን ፡ ሲናገር ፡ ብዙዎች ፡ በእርሱ ፡ አመኑ ።

፴፩ ኢየሱስም ፡ ያመኑትን ፡ አይሁድ ፡— እናንተ ፡ በቃሌ ፡ ብትኖሩ ፡ በእውነት ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቴ ፡ ናችሁ ፤ ፴፪ እውነትንም ፡ ታውቃላችሁ ፡ እውነትም ፡ አርነት ፡ ያወጣችኋል ፡ አላቸው ። ፴፫ እነርሱም ፡ መለሰው ፡— የአብርሃም ፡ ዘር ፡ ነን ፡ ለአንድም ፡ ስንኳ ፡ ከቶ ፡ ባሪያዎች ፡ አልሆንም ፤ አንተ ፡— አርነት ፡ ትወጣላችሁ ፡ እንዴት ፡ ትላለህ ? አሉት ።

፴፬ ኢየሱስ ፡ መለሰ ÷ እንዲህ ፡ ሲል ፡— እውነት ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ÷ ኃጢአት ፡ የሚያደርግ ፡ ሁሉ ፡ የኃጢአት ፡ ባርያ ፡ ነው ። ፴፭ ባርያም ፡ ለዘላለም ፡ በቤት ፡ አይኖርም ፤ ልጁ ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ። ፴፮ እንግዲህ ፡ ልጁ ፡ አርነት ፡ ቢያወጣችሁ ፡ በእውነት ፡ አርነት ፡ ትወጣላችሁ ። ፴፯ የአብርሃም ፡ ዘር ፡ መሆናችሁንስ ፡ አውቃለሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ቃሌ ፡ በእናንተ ፡ አይኖርምና ፡ ልትገድሉኝ ፡ ትፈልጋላችሁ ። ፴፰ እኔ ፡ በአባቴ ፡ ዘንድ ፡ ያየሁትን ፡ እናገራለሁ ፤ እናንተም ፡ ደግሞ ፡ በአባታችሁ ፡ ዘንድ ፡ ያያችሁትን ፡ ታደርጋላችሁ ።

፰ ። ፭ ፤ ዘሌዋ· ፳ ÷ ፲ ፤ ዘዳግ· ፳፪ ÷ ፳፪ ። ፲፪ ፤ ምዕ· ፩ ÷ ፱ ፣ ፭ ፣ ፱ ። ፲፫ ፤ ምዕ· ፭ ÷ ፴፩ ። ፲፬ ፤ ምዕ· ፯ ÷ ፳፰ ። ፲፭ ፤ ምዕ· ፯ ÷ ፳፬ ፤ ፲፪ ÷ ፵፯ ። ፲፯ ፤ ዘዳግ· ፲፱ ÷ ፲፭ ። ፲፰ ፤ ምዕ· ፭ ÷ ፴፯ ። ፲፱ ፤ ምዕ· ፲፬ ÷ ፯ ። ፳ ፤ ምዕ· ፯ ÷ ፰ ። ፳፩ ፤ ምዕ· ፯ ÷ ፴፬ ። ፳፫ ፤ ምዕ· ፯ ÷ ፳፰ ፤ ፫ ÷ ፲፬ ። ፳፰ ፤ ምዕ· ፫ ÷ ፲፬ ። ፴፩ ፤ ምዕ· ፲፭ ÷ ፯ ። ፴፫ ፤ ማቴ· ፫ ÷ ፱ ።

፲፰ እውነት ፡ እውነት ፡ እልሃለሁ ፥ አንተ ፡ ጕልማሳ ፡ ሳለህ ፡ ወገብህን ፡ በገዛ ፡ ራስህ ፡ ታጥቀህ ፡ ወደ ምትወደው ፡ ትሄድ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ስሸመገልህ ፡ ጊዜ ፡ እጆችህን ፡ ትዘረጋለህ ፥ ሌላውም ፡ ያስታጥቅሃል ፡ ወደማትወደውም ፡ ይወስድሃል ፡ ፲፱ አለው ። በምን ፡ ዓይነት ፡ ሞት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያከብር ፡ ዘንድ ፡ እንዳለው ፡ ሲያመለክት ፡ ይህን ፡ አለ ። ይህንም ፡ ብሎ ፡— ተከተለኝ ፡ አለው ።

፳ ጴጥሮስም ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ኢየሱስ ፡ ይወደው ፡ የነበረውን ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ሲከተለው ፡ አየ ፤ እርሱም ፡ ደግሞ ፡ በእራት ፡ ጊዜ ፡ በደረቱ ፡ ተጠግቶ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ አሳልፎ ፡ የሚሰጥህ ፡ ማን ፡ ፳፩ ነው ? ያለው ፡ ነበረ ። ጴጥሮስም ፡ ይህን ፡ አይቶ ፡ ኢየሱስን ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ይህስ ፡ እንዴት ፡ ይሆናል ? አለው ። ኢየሱስም ፡— እስክመጣ ፡ ፳፪ ድረስ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ ብወድስ ፥ ምን ፡ አግዶህ ? አንተ ፡ ተከተለኝ ፡ አለው ። ስለዚህ ፡— ያ ፡ ደቀ ፡ ፳፫ መዝሙር ፡ አይሞትም ፡ የሚለው ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ወንድሞች ፡ ወጣ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ኢየሱስ ፡— እስክመጣ ፡ ድረስ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ ብወድስ ፡ ምን ፡ አግዶህ ? አለው ፡ እንጂ ፡ አይሞትም ፡ አላለውም ።

፳፬ ስለ ፡ እነዚህም ፡ የመሰከረ ፡ ይህንንም ፡ ጽፎ ፡ ያለ ፡ ይህ ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ነው ፤ ምስክሩም ፡ እውነት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እናውቃለን ።

፳፭ ኢየሱስም ፡ ያደረገው ፡ ብዙ ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡ ደግሞ ፡ አለ ፤ ሁሉ ፡ በእያንዳንዱ ፡ ቢጻፍ ፡ ለተጻፉት ፡ መጻሕፍት ፡ ዓለም ፡ ራሱ ፡ ባልበቃቸውም ፡ ይመስለኛል ።

# የሐዋርያት ፡ ሥራ ።

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ ፡ ፩ ቴዎፍሎስ ፡ ሆይ ፥ ኢየሱስ ፡ የመረጣቸውን ፡ ሐዋርያትን ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ካዘዛቸው ፡ በኋላ ፡ እስከ ፡ ዐረገበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፥ ያደርገውና ፡ ያስተምረው ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ጀመረው ፡ ፪ ሁሉ ፡ መጀመሪያውን ፡ ነገር ፡ ጻፍሁ ፤ ደግሞ ፡ አርባ ፡ ቀን ፡ እየታያቸው ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔርም ፡ መንግሥት ፡ ነገር ፡ እየነገራቸው ፥ በብዙ ፡ ማስረጃ ፡ ከሕማማቱ ፡ በኋላ ፡ ሕያው ፡ ሆኖ ፡ ለእ ፬ ነርሱ ፡ ራሱን ፡ አሳያቸው ። ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ አብሮ ፡ ሳለ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ እንዳይወጡ ፡ አዘዛቸው ፥ ነገር ፡ ግን ፡— ከእኔ ፡ የሰማችሁትን ፡ ፭ አብ ፡ የሰጠውን ፡ የተስፋ ፡ ቃል ፡ ጠብቁ ፤ ዮሐንስ ፡ በውኃ ፡ አጥምቆ ፡ ነበርና ፥ እናንተ ፡ ግን ፡ ከጥቂት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ትጠመቃላችሁ ፡ አለ ።

፮ እነርሱም ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ በዚህ ፡ ወራት ፡ ለእስራኤል ፡ መንግሥትን ፡ ትመ ፯ ልሳለህን ? ብለው ፡ ጠየቁት ። እርሱም ፡— አብ ፡ በገዛ ፡ ሥልጣኑ ፡ ያደረገውን ፡ ወራትንና ፡ ዘመናትን ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ ለእናንተ ፡ አልተ ፰ ሰጣችሁም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ በወረደ ፡ ጊዜ ፡ ኃይልን ፡ ትቀበላላችሁ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ በይሁዳም ፡ ሁሉ ፡ በሰማርያም ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርም ፡ ድረስ ፡ ፱ ምስክሮቼ ፡ ትሆናላችሁ ፡ አለ ። ይህንም ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ እነርሱ ፡ እያዩት ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ፤ ደመናም ፡ ከዓይናቸው ፡ ሰውራ ፡ ተቀበለችው ። ፲ እርሱም ፡ ሲሄድ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ትኵር ፡ ብለው ፡ ሲመለከቱ ፡ ሳሉ ፥ እነሆ ፥ ነጫጭ ፡ ልብስ ፡ የለበሱ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ በአጠገባቸው ፡ ቆሙ ፤ ፲፩ ደግሞም ፡— የገሊላ ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ ሰማይ ፡ እየተመለከታችሁ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ቆማችኋል ? ይህ ፡ ከእናንተ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ የወጣው ፡ ኢየሱስ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ሲሄድ ፡ እንዳያችሁት ፥ እንዲሁ ፡ ይመጣል ፡ አሉአቸው ።

፲፪ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡ ከሚባለው ፡ ተራራ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ፥ እርሱም ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ የሰንበት ፡ መንገድ ፡ ያህል ፡ ፲፫ የራቀ ፡ ነው ። በገቡም ፡ ጊዜ ፡ ወደሚኖሩበት ፡ ሰገነት ፡ ወጡ ፥ ጴጥሮስና ፡ ዮሐንስም ፡ ያዕቆብም ፡ እንድርያስም ፥ ፊልጶስም ፥ ቶማስም ፥ በርተሎሜዎስም ፥ ማቴዎስም ፥ የእልፍዮስ ፡ ልጅ ፡ ያዕቆብም ፥ ቀናተኛ ፡ የሚባለው ፡ ስምዖንም ፥ የያዕቆብ ፡ ልጅ ፡ ይሁዳም ። እነዚህ ፡ ፲፬ ሁሉ ፡ ከሴቶችና ፡ ከኢየሱስ ፡ እናት ፡ ከማርያም ፡ ከወንድሞቹም ፡ ጋር ፡ በአንድ ፡ ልብ ፡ ሆነው ፡ ለጸሎት ፡ ይተጉ ፡ ነበር ።

፲፭ በዚህም ፡ ወራት ፡ ጴጥሮስ ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ በሚያህል ፡ በሰዎች ፡ ማኅበር ፡ አብረው ፡ በነበሩ ፡ ፲፮ በወንድሞቹ ፡ መካከል ፡ ተነሥቶ ፡ አለ ፡— ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ኢየሱስን ፡ ለያዙት ፡ መሪ ፡ ስለ ፡ ሆናቸው ፡ ስለ ፡ ይሁዳ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ አስቀድሞ ፡ በዳዊት ፡ አፍ ፡ የተናገረው ፡ የመጽሐፍ ፡ ፲፯ ቃል ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ ይገባ ፡ ነበር ፤ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ተቈጥሮ ፡ ነበርና ፥ ለዚህም ፡ አገልግሎት ፡ ፲፰ ታድሎ ፡ ነበርና ። ይህም ፡ ሰው ፡ በዓመፅ ፡ ዋጋ ፡

፳፩። ፳ ፤ ዮሐ· ፲፫ ፥ ፳፭ ። ፳፪ ፤ ዮሐ· ፲፭ ፥ ፳፯ ፤ ፲፱ ፥ ፴፭ ። ፳፭ ፤ ዮሐ· ፳ ፥ ፴ ።

፩። ፩ ፤ ሉቃ· ፩ ፥ ፩—፬ ። ፪ ፤ ፫ ፤ ማቴ· ፳፰ ፥ ፲፱ ፤ ፳ ፤ ሉቃ· ፳፬ ፥ ፴፮—፵፫ ፤ ፮ ፤ ፶፩ ፤ ዮሐ· ፳ ፥ ፲፱ ፤ ፳፮ ፤ ፳፩ ፥ ፲፬ ። ፬ ፤ ሉቃ· ፳፬ ፥ ፵፱ ፤ ዮሐ· ፲፬ ፥ ፲፯ ፤ ፳፮ ። ፭ ፤ ዮሐ· ፩ ፥ ፴፫ ፤ ማቴ· ፫ ፥ ፲፩ ። ፯ ፤ ሉቃ· ፲፪ ፥ ፲፩ ፤ ፳፪ ፥ ፳፫ ። ፰ ፤ ማቴ· ፳፬ ፥ ፴፯ ። ፱ ፤ ሉቃ· ፳፬ ፥ ፶፩ ። ፲ ፤ ማር· ፲፮ ፥ ፲፱ ። ፲፩ ፤ ማር· ፲፱ ፥ ፳፬ ። ፲፫ ፤ ማቴ· ፲ ፥ ፪—፬ ። ፲፬ ፤ ማቴ· ፲፫ ፥ ፶፭ ፤ ማር· ፲፱ ፥ ፵ ፤ ፵፩ ፤ ሉቃ· ፰ ፥ ፪ ፤ ፫ ። ፲፮—፲፱ ፤ ማቴ· ፳፯ ፥ ፫—፲ ።

፲፰ እውነት ፡ እውነት ፡ እልሃለሁ ፥ አንተ ፡ ጐልማሳ ፡ ሳለህ ፡ ወገብህን ፡ በገዛ ፡ ራስህ ፡ ታጥቀህ ፡ ወደ ምትወደው ፡ ትሄድ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በሸመገልህ ፡ ጊዜ ፡ እጆችህን ፡ ትዘረጋለህ ፥ ሌላውም ፡ ያስታጥቅሃል ፡ ወደማትወደውም ፡ ይወስድሃል ፡ ፲፱ አለው ። በምን ፡ ዓይነት ፡ ሞት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያከብር ፡ ዘንድ ፡ እንዳለው ፡ ሲያመለክት ፡ ይህን ፡ አለ ። ይህንም ፡ ብሎ ፡— ተከተለኝ ፡ አለው ።

፳ ጴጥሮስም ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ኢየሱስ ፡ ይወደው ፡ የነበረውን ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ሲከተለው ፡ አየ ፤ እርሱም ፡ ደግሞ ፡ በእራት ፡ ጊዜ ፡ በደረቱ ፡ ተጠግቶ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ አሳልፎ ፡ የሚሰጥህ ፡ ማን ፡ ነው ? ያለው ፡ ነበረ ። ፳፩ ጴጥሮስም ፡ ይህን ፡ አይቶ ፡ ኢየሱስን ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ይህስ ፡ እንዴት ፡ ይሆናል ? አለው ። ፳፪ ኢየሱስም ፡— እስክመጣ ፡ ድረስ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ ብወድስ ፥ ምን ፡ አግዶህ ? አንተ ፡ ተከተለኝ ፡ አለው ። ፳፫ ስለዚህ ፡— ያ ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ አይሞትም ፡ የሚለው ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ወንድሞች ፡ ወጣ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ኢየሱስ ፡— እስክመጣ ፡ ድረስ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ ብወድስ ፡ ምን ፡ አግዶህ ? አለው ፡ እንጂ ፡ አይሞትም ፡ አላለውም ።

፳፬ ስለ ፡ እነዚህም ፡ የመሰከረ ፡ ይህንንም ፡ የጻፈ ፡ ያለ ፡ ይህ ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ነው ፥ ምስክሩም ፡ እውነት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እናውቃለን ።

፳፭ ኢየሱስም ፡ ያደረገው ፡ ብዙ ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡ ደግሞ ፡ አለ ፤ ሁሉ ፡ በእያንዳንዱ ፡ ቢጻፍ ፡ ስለ ተጻፉት ፡ መጻሕፍት ፡ ዓለም ፡ ራሱ ፡ ባልበቃቸውም ፡ ይመስለኛል ።

# የሐዋርያት ፡ ሥራ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ ቴዎፍሎስ ፡ ሆይ ፥ ኢየሱስ ፡ የመረጣቸውን ፡ ሐዋርያትን ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ካዘዛቸው ፡ በኋላ ፡ እስከ ፡ ዐረገበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፥ ያደርገውና ፡ ያስተምረው ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ጀመረው ፡ ፪ ሁሉ ፡ መጀመሪያውን ፡ ነገር ፡ ጻፍሁ ፤ ደግሞ ፡ አርባ ፡ ቀን ፡ እየታያቸው ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔርም ፡ መንግሥት ፡ ነገር ፡ እየነገራቸው ፥ በብዙ ፡ ማስረጃ ፡ ከሕማማቱ ፡ በኋላ ፡ ሕያው ፡ ሆኖ ፡ ለእ ፫ ነርሱ ፡ ራሱን ፡ አሳያቸው ። ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ አብሮ ፡ ሳለ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ እንዳይወጡ ፡ እዘ ፬ ዛቸው ፥ ነገር ፡ ግን ፡— ከእኔ ፡ የሰማችሁትን ፡ አብ ፡ የሰጠውን ፡ የተስፋ ፡ ቃል ፡ ጠብቁ ፤ ዮሐ ፭ ንስ ፡ በውኃ ፡ አጥምቆ ፡ ነበርና ፥ እናንተ ፡ ግን ፡ ከጥቂት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ትጠመቃላችሁ ፡ አለ ።

፮ እነርሱም ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ በዚህ ፡ ወራት ፡ ለእስራኤል ፡ መንግሥትን ፡ ትመ ፯ ልሳለህን ? ብለው ፡ ጠየቁት ። እርሱም ፡— አብ ፡ በገዛ ፡ ሥልጣኑ ፡ ያደረገውን ፡ ወራትንና ፡ ዘመናትን ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ ለእናንተ ፡ አልተ ፰ ሰጣችሁም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ በወረደ ፡ ጊዜ ፡ ኃይልን ፡ ትቀበላላችሁ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ በይሁዳም ፡ ሁሉ ፡ በሰማርያም ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርም ፡ ድረስ ፡ ፱ ምስክሮቼ ፡ ትሆናላችሁ ፡ አለ ። ይህንም ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ እነርሱ ፡ እያዩት ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ፤ ደመናም ፡ ከዓይናቸው ፡ ሰውራ ፡ ተቀበለችው ። ፲ እርሱም ፡ ሲሄድ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ትኵር ፡ ብለው ፡ ሲመለከቱ ፡ ሳሉ ፥ እነሆ ፥ ነጭ ፡ ልብስ ፡ የለበሱ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ በአጠገባቸው ፡ ቆሙ ፤ ፲፩ ደግሞም ፡— የገሊላ ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ ሰማይ ፡ እየተመለከታችሁ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ቆማችኋል ? ይህ ፡ ከእናንተ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ የወጣው ፡ ኢየሱስ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ሲሄድ ፡ እንዳያችሁት ፥ እንዲሁ ፡ ይመጣል ፡ አሉአቸው ።

፲፪ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡ ከሚባለው ፡ ተራራ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ፥ እርሱም ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ የሰንበት ፡ መንገድ ፡ ያህል ፡ የራቀ ፡ ነው ። ፲፫ በገቡም ፡ ጊዜ ፡ ወደሚኖሩበት ፡ ሰገነት ፡ ወጡ ፥ ጴጥሮስና ፡ ዮሐንስም ፡ ያዕቆብም ፡ እንድርያስም ፥ ፊልጶስም ፥ ቶማስም ፥ በርተሎሜዎስም ፥ ማቴዎስም ፥ የእልፍዮስ ፡ ልጅ ፡ ያዕቆብም ፥ ቀናተኛ ፡ የሚባለው ፡ ስምዖንም ፥ የያዕቆብ ፡ ልጅ ፡ ይሁዳም ። ፲፬ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ከሴቶችና ፡ ከኢየሱስ ፡ እናት ፡ ከማርያም ፡ ከወንድሞቹም ፡ ጋር ፡ በአንድ ፡ ልብ ፡ ሆነው ፡ ለጸሎት ፡ ይተጉ ፡ ነበር ።

፲፭ በዚህም ፡ ወራት ፡ ጴጥሮስ ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ በሚያህል ፡ በሰዎች ፡ ማኅበር ፡ አብረው ፡ በነበሩ ፡ ፲፮ በወንድሞቹ ፡ መካከል ፡ ተነሥቶ ፡ አለ ፡— ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ኢየሱስን ፡ ለያዙት ፡ መሪ ፡ ስለ ፡ ሆናቸው ፡ ስለ ፡ ይሁዳ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ አስቀድሞ ፡ በዳዊት ፡ አፍ ፡ የተናገረው ፡ የመጽሐፍ ፡ ቃል ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ ይገባ ፡ ነበር ፤ ፲፯ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ተቈጥሮ ፡ ነበርና ፥ ለዚህም ፡ አገልግሎት ፡ ታድሎ ፡ ነበርና ። ፲፰ ይህም ፡ ሰው ፡ በዓመፃ ፡ ዋጋ ፡

፳፩ ። ፳ ፤ ምዕ· ፲፫ ፥ ፳፭ ። ፳፬ ፤ ምዕ· ፲፱ ፥ ፴፭ ፤ ፲፬ ፥ ፵፭ ። ፳፭ ፤ ምዕ· ፳ ፥ ፴ ።

፩ ። ፩ ፤ ሉቃ· ፩ ፥ ፩—፬ ። ፪ ፡ ፫ ፤ ማቴ· ፳፰ ፥ ፲፱ ፡ ፳ ፤ ሉቃ· ፳፬ ፥ ፴፮—፵፫ ፡ ፱ ፡ ፶፩ ፤ ዮሐ· ፳ ፥ ፲፱ ፡ ፳፮ ፡ ፳፯ ፥ ፲፱ ። ፬ ፤ ሉቃ· ፳፬ ፥ ፵፱ ፤ ዮሐ· ፲፬ ፥ ፲፮ ፡ ፳፮ ። ፭ ፤ ምዕ· ፪ ፥ ፪ ፤ ማቴ· ፫ ፥ ፲፩ ። ፯ ፤ ሉቃ· ፲፱ ፥ ፲፩ ፤ ፳፬ ፥ ፳፩ ። ፰ ፤ ማቴ· ፳፬ ፥ ፲፬ ። ፱ ፤ ሉቃ· ፳፬ ፥ ፶፩ ። ፲ ፤ ማር· ፲፮ ፥ ፲፱ ። ፲፩ ፤ ማር· ፲፬ ፥ ፳፯ ። ፲፫ ፤ ማቴ· ፲ ፥ ፪—፬ ። ፲፬ ፤ ማቴ· ፲፫ ፥ ፶፭ ፤ ማር· ፲፭ ፥ ፵ ፡ ፵፯ ፤ ሉቃ· ፰ ፥ ፪ ፡ ፫ ። ፲፮—፳ ፤ ማቴ· ፳፯ ፥ ፫—፲ ።

መሬት ፡ ገዛ ፡ በግንባሩም ፡ ተደፍቶ ፡ ከመካከሉ ፡ ተሰነጠቀ ፡ አንጀቱም ፡ ሁሉ ፡ ተዘረገፈ ፤ ፲፱ በኢየሩሳሌምም ፡ ለሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ታወቀ ፤ ስለዚህም ፡ ያ ፡ መሬት ፡ በቋንቋቸው ፡ አኬልዳማ ፡ ተብሎ ፡ ተጠራ ፥ እርሱም ፡ የደም ፡ መሬት ፡ ማለት ፡ ነው ። ፳ በመዝሙር ፡ መጽሐፍ ፡— መኖሪያው ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ትሁን ፡ የሚኖርበትም ፡ አይኑር ፤ ደግሞም ፡— ሹመቱን ፡ ሌላ ፡ ይውሰዳት ፡ ተብሎ ፡ ተጽፎአልና ። ፳፩፡፳፪ ስለዚህ ፡ ከዮሐንስ ፡ ጥምቀት ፡ ጀምሮ ፡ ከእኛ ፡ ዘንድ ፡ እስከ ፡ ረገበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፥ ጌታ ፡ ኢየሱስ ፡ በእኛ ፡ መካከል ፡ ሲገባበትና ፡ በወጣበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ አብረው ፡ ከነበሩት ፡ ሰዎች ፥ ከእነዚህ ፡ አንዱ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ የትንሣኤው ፡ ምስክር ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ። ፳፫ ኢዮስጦስም ፡ የሚሉትን ፡ በርስያን ፡ የተባለውን ፡ ዮሴፍንና ፡ ማትያስን ፡ ሁለቱን ፡ አቆሙ ። ፳፬፡፳፭ ሲጸልዩም ፡— የሁሉን ፡ ልብ ፡ የምታውቅ ፡ አንተ ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ይሁዳ ፡ ወደ ፡ ገዛ ፡ ራሱ ፡ ስፍራ ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ በተዋት ፡ በዚህች ፡ አገልግሎትና ፡ ሐዋርያነት ፡ ስፍራን ፡ እንዲቀበል ፡ የመረጥኸውን ፡ ከእነዚህ ፡ ከሁለቱ ፡ አንዱን ፡ ሹመው ፡ አሉ ። ፳፮ ዕጣም ፡ ተጣጣሉላቸው ፥ ዕጣውም ፡ ለማትያስ ፡ ወደቀና ፡ ከአሥራ ፡ አንዱ ፡ ሐዋርያት ፡ ጋር ፡ ተቈጠረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ በዓለ ፡ ኀምሳ ፡ የተባለውም ፡ ቀን ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፥ ሁሉም ፡ በአንድ ፡ ልብ ፡ ሆነው ፡ አብረው ፡ ሳሉ ፥ ፪ ድንገት ፡ እንደሚነጥቅ ፡ ዓውሎ ፡ ነፋስ ፡ ከሰማይ ፡ ድምፅ ፡ መጣ ፥ ተቀምጠው ፡ የነበሩበትንም ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ሞላው ። ፫ እንደ ፡ እሳትም ፡ የተከፋፈሉ ፡ ልሳኖች ፡ ታዩአቸው ፤ በያንዳንዳቸውም ፡ ላይ ፡ ተቀመጡባቸው ። ፬ በሁሉም ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሞላባቸው ፥ መንፈስም ፡ ይናገሩ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ሰጣቸው ፡ በሌላ ፡ ልሳኖች ፡ ይናገሩ ፡ ጀመር ።

፭ ከሰማይም ፡ በታች ፡ ካሉ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ በጸሎት ፡ የተጉ ፡ አይሁድ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ይኖሩ ፡ ነበር ፤ ፮ ይህም ፡ ድምፅ ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ተሰበሰቡ ፥ እያንዳንዱም ፡ በገዛ ፡ ቋንቋው ፡ ሲናገሩ ፡ ይሰማ ፡ ስለ ፡ ነበር ፡ የሚሉትን ፡ አጡ ። ፯ ተገርመውም ፡ ተደንቀውም ፡ እንዲህ ፡ አሉ ፡— እነሆ ፥ እነዚህ ፡ የሚናገሩት ፡ ሁሉ ፡ የገሊላ ፡ ሰዎች ፡ አይደሉምን ? ፰ እኛም ፡ እያንዳንዳችን ፡ የተወለድንበትን ፡ የገዛ ፡ ቋንቋችንን ፡ እንዴት ፡ እንሰማለን ? ፱ የጳርቴና ፡ የሜድ ፡ የኢላሜጤም ፡ ሰዎች ፥ በሁለት ፡ ወንዝም ፡ መካከል ፡ በይሁዳም ፡ በቀጰዶቅያም ፡ በጳንጦስም ፡ ፲ በእስያም ፥ በፍርግያም ፡ በጵንፍልያም ፡ በግብፅም ፡ በቀሬናም ፡ በኩል ፡ ባሉት ፡ በሊቢያ ፡ ወረዳዎች ፡ የምንኖር ፥ ስሮሜም ፡ የምንቀመጥ ፥ ፲፩ አይሁድም ፡ ወደ ፡ ይሁዲነትም ፡ የገባን ፥ የቀርጤስና ፡ የዓረብ ፡ ሰዎች ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ታላቅ ፡ ሥራ ፡ በልሳኖቻችን ፡ ሲናገሩ ፡ እንሰማቸዋለን ። ፲፪ ሁሉም ፡ ተገረሙና ፡ አመንትተው ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡— እንጃ ፡ ይህ ፡ ምን ፡ ይሆን ? ፲፫ አሉ ። ሌሎች ፡ ግን ፡ እያፌዙባቸው ፡— ጉሽ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ጠግበዋል ፡ አሉ ።

፲፬ ነገር ፡ ግን ፡ ጴጥሮስ ፡ ከአሥራ ፡ አንዱ ፡ ጋር ፡ ቆመ ፥ ድምፁንም ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ ተናገራቸው ፡— አይሁድ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ የምትኖሩ ፡ ሁላችሁ ፥ ይህ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ የታወቀ ፡ ይሁን ፥ ቃሎቼንም ፡ አድምጡ ። ፲፭ ለእናንተ ፡ እንደ ፡ መሰላችሁ ፡ እነዚህ ፡ የሰከሩ ፡ አይደሉም ፥ ከቀኑ ፡ ሦስተኛ ፡ ሰዓት ፡ ነውና ፤ ፲፮ ነገር ፡ ግን ፡ ይህ ፡ በነቢዩ ፡ በኢዩኤል ፡ የተባለው ፡ ነው ፡—

፲፯ እግዚአብሔር ፡ ይላል ፡— በመጨረሻው ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ፤ ሥጋ ፡ በለበሰ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከመንፈሴ ፡ አፈስሳለሁ ፤ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችሁም ፡ ትንቢት ፡ ይናገራሉ ፥ ጐበዞቻችሁም ፡ ራእይ ፡ ያያሉ ፥ ሽማግሌዎቻችሁም ፡ ሕልም ፡ ያልማሉ ፤ ፲፰ ደግሞም ፡ በዚያች ፡ ወራት ፡ በወንዶችና ፡ በሴቶች ፡ ባሪያዎቼ ፡ ላይ ፡ ከመንፈሴ ፡ አፈስሳለሁ ፡ ትንቢትም ፡ ይናገራሉ ። ፲፱ ድንቆችን ፡ በላይ ፡ በሰማይ ፥ ምልክቶችንም ፡ በታች ፡ በምድር ፡ እሰጣለሁ ፤ ደምም ፡ እሳትም ፡ የጢስ ፡ጭጋግም ፡ ይሆናል ፤ ፳ ታላቅ ፡ የሆነ ፡ የተገለጠም ፡ የጌታ ፡ ቀን ፡ ሳይመጣ ፡ ፀሐይ ፡ ወደ ፡ ጨለማ ፡ ጨረቃም ፡ ወደ ፡ ደም ፡ ይለወጣሉ ። ፳፩ የጌታን ፡ ስም ፡ የሚጠራም ፡ ሁሉ ፡ ይድናል ።

፳፪ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ ቃል ፡ ስሙ ፤ ራሳችሁ ፡ እንደምታውቁ ፥ የናዝሬቱ ፡ ኢየሱስ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመካከላችሁ ፡ በእርሱ ፡ በኩል ፡ በደረገው ፡ ተአምራትና ፡ በድንቆች ፡ በምልክቶችም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ለእናንተ ፡ የተገለጠ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤ ፳፫ እርሱንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ በተወሰነው ፡ አሳቡና ፡ በቀደመው ፡ እውቀቱ ፡ ተሰጥቶ ፡ በዓመፀኞች ፡ እጅ ፡ ሰቅላችሁ ፡ ገደላችሁት ። ፳፬ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ የሞትን ፡ ጣር ፡ አጥፍቶ ፡ አስነሣው ፥ ሞት ፡ ይይዘው ፡ ዘንድ ፡ አልቻለምና ። ፳፭ ዳዊት ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡—

ጌታን ፡ ሁልጊዜ ፡ በፊቴ ፡ አየሁት ፥ እንዳልታወክ ፡ በቀኜ ፡ ነውና ። ፳፮ ስለዚህ ፡ ልቤን ፡ ደስ ፡ አለው ፥ ልሳኔም ፡ሐሤት ፡ አደረገ ፥ ደግሞም ፡ ሥጋዬ ፡ በተስፋ ፡ ያድራል ፤ ፳፯ ነፍሴን ፡ በሲኦል ፡ አትተዋትምና ፥ ቅዱስህንም ፡ መበስበስን ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ አትሰ

፩። ፳ ፤ መዝ. ፷፰ ፥ ፳፭ ፤ ፻፱ ፥ ፰። ፳፭ ፤ ዮሐ. ፲፬ ፥ ፳፮። ፳፮ ፤ ፩ ዜና. ፳፭ ፥ ፱። ፳፯ ፤ ምሳ. ፲፮ ፥ ፴፫።
፪። ፩ ፤ ዘሌዋ. ፳፫ ፥ ፲፭ ፤ ፲፮። ፫ ፤ ማቴ. ፫ ፥ ፲፩። ፲፯—፳፩ ፤ ኢዩ. ፪ ፥ ፳፰—፴፪። ፳፪ ፤ ዮሐ. ፫ ፥ ፪። ፳፫ ፤ ሉቃ ፳፪ ፥ ፳፪። ፳፭—፳፰ ፤ መዝ. ፲፭ ፥ ፰—፲፩።

፳፰ ጠውም ። የሕይወትን ፡ መንገድ ፡ አስታ
ወቅኸኝ ፤ ከፊትህ ፡ ጋር ፡ ደስታን ፡ ትሞ
ላብኛለህ ።

፳፱ ወንድሞች ፡ ሆይ ÷ ስለ ፡ አባቶች ፡ አለቃ ፡ ስለ ፡ ዳዊት ፡ እንደ ፡ ሞተም ፡ እንደ ፡ ተቀበረም ፡ ለእናንተ ፡ በግልጥ ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ ፍቀዱልኝ ፤ መቃብሩም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ፴ ነቢይ ፡ ስለ ፡ ሆነ ÷ ከወገቡም ፡ ፍሬ ፡ በዙፋኑ ፡ ያስቀምጥ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ መሐላ ፡ ፴፩ እንደ ፡ ማለለት ፡ ስለ ፡ አወቀ ÷ ስለ ፡ ክርስቶስ ፡ ትንሣኤ ፡ አስቀድሞ ፡ አይቶ ÷ ነፍሱ ፡ በሲኦል ፡ እንዳልቀረች ፡ ሥጋውም ፡ መበስበስን ፡ እንዳ ፴፪ ላየ ፡ ተናገረ ። ይህን ፡ ኢየሱስን ፡ እግዚአብ ሔር ፡ አስነሣው ፡ ለዚህም ፡ ነገር ፡ እኛ ፡ ሁላ ፴፫ ችን ፡ ምስክሮች ፡ ነን ፤ ስለዚህ ፡ በእግዚአብ ሔር ፡ ቀኝ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎና ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱ ስን ፡ የተስፋ ፡ ቃል ፡ ከአብ ፡ ተቀብሎ ፡ ይህን ፡ እናንተ ፡ አሁን ፡ የምታዩትንና ፡ የምትሰሙትን ፡ ፴፬፡፴፭ አፈሰሰው ። ዳዊት ፡ ወደ ፡ ሰማያት ፡ አልወጣ ምና ÷ ነገር ፡ ግን ፡ እርሱ ፡—

ጌታ ፡ ጌታዬን ፡— ጠላቶችህን ፡ የእግርህ ፡
መረገጫ ፡ እስካደርግልህ ፡ ድረስ ፡ በቀኜ ፡
ተቀመጥ ፡ አለው ፡

፴፮ አለ ። እንግዲህ ፡ ይህን ፡ እናንተ ፡ የሰቀላችሁ ትን ፡ ኢየሱስን ፡ እግዚአብሔር ፡ ጌታም ፡ ክር ስቶስም ፡ እንዳደረገው ፡ የእስራኤል ፡ ወገን ፡ ሁሉ ፡ በእርግጥ ፡ ይወቅ ።

፴፯ ይህንም ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ልባቸው ፡ ተነከ ÷ ጴጥሮስንና ፡ ሌሎችንም ፡ ሐዋርያት ፡— ወንድ ሞች ፡ ሆይ ÷ ምን ፡ እናድርግ ? አሉአቸው ። ፴፰ ጴጥሮስም ፡— ንስሐ ፡ ግቡ ÷ ኃጢአታችሁም ፡ ይሰረይ ፡ ዘንድ ፡ እያንዳንዳችሁ ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስም ፡ ተጠመቁ ፤ የመንፈስ ፡ ቅዱስ ፴፱ ንም ፡ ስጦታ ፡ ትቀበላላችሁ ። የተስፋው ፡ ቃል ፡ ለእናንተና ፡ ለልጆቻችሁ ፡ ጌታ ፡ አምላካችንም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ለሚጠራቸው ፡ በሩቅ ፡ ላሉ ፡ ሁሉ ፡ ፵ ነውና ፡ አላቸው ። በብዙ ፡ ሌላ ፡ ቃልም ፡ መሰ ከረና ፡— ከዚህ ፡ ጠማማ ፡ ትውልድ ፡ ዳኑ ፡ ብሎ ፡ ፵፩ መከራቸው ። ቃሉንም ፡ የተቀበሉ ፡ ተጠመቁ ÷ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡ የሚያህል ፡ ነፍስ ፡ ፵፪ ተጨመሩ ፤ በሐዋርያትም ፡ ትምህርትና ፡ በኅ ብረት ፡ እንጀራውንም ፡ በመቍረስ ፡ በየጸሎ ቱም ፡ ይተጉ ፡ ነበር ።

፵፫ ነገር ፡ ግን ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡ ፍርሃት ፡ ሆነ ፤ በሐዋርያትም ፡ እጅ ፡ ብዙ ፡ ድንቅና ፡ ምልክት ፡ ፵፬ ተደረገ ። ያመኑትም ፡ ሁሉ ፡ አብረው ፡ ነበሩ ፤ ፵፭ ያላቸውንም ፡ ሁሉ ፡ አንድነት ፡ አደረጉ ። መሬ ታቸውንና ፡ ጥሪታቸውንም ፡ እየሸጡ ÷ ማን ኛውም ፡ እንደሚፈልግ ፡ ለሁሉ ፡ ያካፍሉት ፡ ፵፮ ነበር ። በየቀኑም ፡ በአንድ ፡ ልብ ፡ ሆነው ፡ በመ ቅደስ ፡ እየተጉ ፡ በቤታቸውም ፡ እንጀራ ፡ እየ ቈረሱ ÷ በደስታና ፡ በጥሩ ፡ ልብ ፡ ምግባቸውን ፡ ፵፯ ይመገቡ ፡ ነበር ፤ እግዚአብሔርንም ፡ እያመሰ ገኑ ፡ በሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ሞገስ ፡ ነበራቸው ። ጌታም ፡ የሚድኑትን ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ይጨምር ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ጴጥሮስና ፡ ዮሐንስም ፡ በጸሎት ፡ ጊዜ ፡ በዘ ጠኝ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ ይወጡ ፡ ነበር ። ፪ ወደ ፡ መቅደስም ፡ ከሚገቡት ፡ ምጽዋት ፡ ይለ ምን ፡ ዘንድ ÷ ሰዎች ፡ ተሸክመው ፡ መልካም ፡ በሚሉአት ፡ በመቅደስ ፡ ደጅ ፡ በየቀኑ ፡ ያስቀም ጡት ፡ የነበሩ ፡ ከእናቱ ፡ ማኅፀን ፡ ጀምሮ ፡ አንካሳ ፡ ፫ የሆነ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበረ ። እርሱም ፡ ጴጥሮስና ፡ ዮሐንስ ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ ሊገቡ ፡ እንዳላቸው ፡ ፬ ባየ ፡ ጊዜ ÷ ምጽዋትን ፡ ለመናቸው ። ጴጥ ሮስም ፡ ከዮሐንስ ፡ ጋር ፡ ትኵር ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ተመልክቶ ፡— ወደ ፡ እኛ ፡ ተመልከት ፡ ፭ አለው ። እርሱም ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ከእነርሱ ፡ እንዲቀበል ፡ ሲጠብቅ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ተመለ ፮ ከተ ። ጴጥሮስ ፡ ግን ፡— ብርና ፡ ወርቅ ፡ የለኝም ፤ ይህን ፡ ያለኝን ፡ ግን ፡ እሰጥሃለሁ ፤ በናዝሬቱ ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስም ፡ ተነሣና ፡ ተመ ፯ ላለስ ፡ አለው ። በቀኝ ፡ እጁም ፡ ይዞ ፡ አስነ ሣው ፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ እግሩና ፡ ቍርጭም ፰ ጭምቱ ፡ ጸና ÷ ወደ ፡ ላይ ፡ ዘሎም ፡ ቆመ ÷ ይመላለስም ፡ ጀመር ፤ እየተመላለሰም ፡ እየዘለ ለም ፡ እግዚአብሔርንም ፡ እያመሰገነ ፡ ከእነርሱ ፡ ፱ ጋር ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ ገባ ። ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እያመሰገነ ፡ ሲመላለስ ፡ አዩት ፤ ፲ መልክምም ፡ በሚሉአት ፡ በመቅደስ ፡ ደጅ ፡ ስለ ፡ ምጽዋት ፡ ተቀምጦ ፡ የነበረው ፡ እርሱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አወቁት ፤ በእርሱም ፡ ከሆነው ፡ የተነሣ ፡ መደነቅና ፡ መገረም ፡ ሞላባቸው ።

፲፩ እርሱም ፡ ጴጥሮስንና ፡ ዮሐንስን ፡ ይዞ ፡ ሳለ ÷ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ እየተደነቁ ፡ የሰሎሞን ፡ ደጅ ፡ መመላለሻ ፡ በሚባለው ፡ አብረው ፡ ወደ ፡ እነ ፲፪ ርሱ ፡ ሮጡ ። ጴጥሮስም ፡ አይቶ ፡ ለሕዝቡ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መለሰ ፡— የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ÷ በዚህ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትደነቃላችሁ ? ወይስ ፡ በገዛ ፡ ኃይላችን ፡ ወይስ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በመ ፍራታችን ፡ ይህ ፡ ይመላለስ ፡ ዘንድ ፡ እንዳደረ ግነው ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትኵር ፡ ብላችሁ ፡ ታዩና ፲፫ ላችሁ ? የአብርሃምና ፡ የይስሐቅ ፡ የያዕቆብም ፡ አምላክ ÷ የአባቶቻችን ፡ አምላክ ÷ እናንተ ፡ አሳ ልፋችሁ ፡ የሰጣችሁትንና ፡ ሊፈታው ፡ ቈርጦ ፡ ሳለ ፡ በጲላጦስ ፡ ፊት ፡ የካዳችሁትን ፡ ብላቴና ፲፬ ውን ፡ ኢየሱስን ፡ አከበረው ። እናንተ ፡ ግን ፡ ቅዱሱን ፡ ጻድቁንም ፡ ክዳችሁ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳዩን ፡

፪። ፳፰ ፤ ፩ ነገሥ. ፪ ÷ ፲ ፤ ነህ. ፫ ÷ ፲፮ ። ፴ ፤ መዝ. ፻፴፩ ÷ ፲፩ ። ፴፬ ፡ ፴፭ ፤ መዝ. ፻፱ ÷ ፩ ። ፴፰ ፤ ማቴ. ፳፰ ÷ ፲፱ ፤ ሉቃ. ፳፬ ÷ ፵፯ ፤ ዮሐ. ፯ ÷ ፴፱ ። ፵ ፤ ማቴ. ፲፯ ÷ ፲፯ ። ፵፬ ፤ ሉቃ. ፳፬ ÷ ፲፱ ። ፵፬ ፤ ምዕ. ፬ ÷ ፴፪ ። ፵፮ ፤ ቀ. ፵፪ ።
፫። ፫ ፤ ኢሳ. ፵፩ ÷ ፯ ። ፲፩ ፤ ዮሐ. ፲ ÷ ፳፫ ። ፲፫—፲፭ ፤ ምዕ. ፪ ÷ ፳፪—፳፬ ። ፲፫ ፤ ዘፀአ. ፫ ÷ ፮ ፤ ሉቃ. ፳፫ ፡ ፲፰ ፡ ፳፭ ። ፲፬ ፤ ሉቃ. ፳፫ ÷ ፲፰ ፡ ፲፱ ።

፲፭ ሰው ፡ ይሰጣችሁ ፡ ዘንድ ፡ ለመናችሁ ፥ የሕይወትንም ፡ ራስ ፡ ገደላችሁት ፤ እርሱን ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሙታን ፡ አስነሣው ፥ ለዚህም ፡
፲፮ ነገር ፡ እኛ ፡ ምስክሮች ፡ ነን ። በስሙም ፡ በማመን ፡ ይህን ፡ የምታዩትንና ፡ የምታውቁትን ፡ የእርሱ ፡ ስም ፡ አጸናው ፥ በእርሱም ፡ በኩል ፡ የሆነው ፡ እምነት ፡ በሁላችሁ ፡ ፊት ፡ ይህን ፡ ፍጹም ፡ ጤና ፡ ሰጠው ።
፲፯ አሁንም ፥ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፥ እናንተ ፡ እንደ ፡ አለቆቻችሁ ፡ ደግሞ ፡ ባለማወቅ ፡ እንዳደረጋ
፲፰ ችሁት ፡ አውቃለሁ ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ክርስቶስ ፡ መከራ ፡ እንዲቀበል ፡ አስቀድሞ ፡ በነቢያት ፡ ሁሉ ፡ አፍ ፡ የተናገረውን ፡ እንዲሁ ፡ ፈጸ
፲፱፡፳ መው ። እንግዲህ ፡ ከጌታ ፡ ፊት ፡ የመጽናናት ፡ ዘመን ፡ እንድትመጣላችሁ ፡ አስቀድሞም ፡ ለእናንተ ፡ የመረጠውን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ እንዲልክላችሁ ፥ ኃጢአታችሁ ፡ ይደመሰስ ፡ ዘንድ ፡
፳፩ ንስሐ ፡ ግቡ ፡ ተመለሱም ። እግዚአብሔር ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ በቅዱሳን ፡ ነቢያቱ ፡ አፍ ፡ የተናገረው ፥ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እስከሚታደስበት ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ ሰማይ ፡ ይቀበለው ፡ ዘንድ ፡ ይገባልና ።
፳፪ ሙሴም ፡ ለአባቶች ፡— ጌታ ፡ አምላክ ፡ እኔን ፡ እንዳስነሣኝ ፡ ነቢይን ፡ ከወንድሞቻችሁ ፡ ያስነሣላችኋል ፤ በሚነግራችሁ ፡ ሁሉ ፡ እርሱን ፡
፳፫ ስሙት ። ያንም ፡ ነቢይ ፡ የማትሰማው ፡ ነፍስ ፡ ሁሉ ፡ ከሕዝብ ፡ ተለይታ ፡ ትጠፋለች ፡ አለ ።
፳፬ ሁለተኛም ፡ ከሳሙኤል ፡ ጀምሮ ፡ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ የተናገሩት ፡ ነቢያት ፡ ሁሉ ፡ ደግሞ ፡ ስለ
፳፭ ዚህ ፡ ወራት ፡ ተናገሩ ። እናንተ ፡ የነቢያት ፡ ልጆችና ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአብርሃም ፡— በዘርህ ፡ የምድር ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ ይባረካሉ ፡ ብሎ ፥ ከአባቶቻችን ፡ ጋር ፡ ያደረገው ፡ የኪዳን ፡ ልጆች ፡
፳፮ ናችሁ ። ለእናንተ ፡ አስቀድሞ ፡ እግዚአብሔር ፡ ብላቴናውን ፡ አስነሥቶ ፥ እያንዳንዳችሁን ፡ ከክፋታችሁ ፡ እየመለሰ ፡ ይባርካችሁ ፡ ዘንድ ፥ ላከው ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ለሕዝቡም ፡ ሲናገሩ ፡ የካህናት ፡ አለቆችና ፡
፪ የመቅደስ ፡ አዛዥ ፡ ሰዱቃውያንም ፥ ሕዝቡን ፡ ስለ ፡ አስተማሩና ፡ በኢየሱስ ፡ የሙታንን ፡ ትንሣኤ ፡ ስለ ፡ ሰበኩ ፡ ተቈጥተው ፥ ወደ ፡ እነርሱ ፡
፫ ቀረቡ ፥ እጃቸውንም ፡ ጫኑባቸው ፡ አሁን ፡ መሸቶ ፡ ነበርና ፡ እስከ ፡ ማግሥቱ ፡ ድረስ ፡ በወ
፬ ኅኒ ፡ አኖሩአቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ ቃሉን ፡ ከሰሙት ፡ ብዙዎች ፡ አመኑ ፥ የወንዶችም ፡ ቍጥር ፡ አምስት ፡ ሺህ ፡ ያህል ፡ ሆነ ።
፭፡፮ በነገውም ፡ አለቆቻቸውና ፡ ሽማግሌዎች ፡ ጻፎችም ፡ ሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ ሐናም ፡ ቀያፋም ፡ ዮሐንስም ፡ እስክንድሮስም ፡ የሊቀ ፡ ካህናቱም ፡ ዘመዶች ፡ የነበሩት ፡ ሁሉ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተሰበ
፯ ሰቡ ፤ እነርሱንም ፡ በመካከል ፡ አቁመው ፡— በምን ፡ ኃይል ፡ ወይስ ፡ በማን ፡ ስም ፡ እናንተ ፡ ይህን ፡ አደረጋችሁ ? ብለው ፡ ጠየቁአቸው ።
፰ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ጴጥሮስ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ተሞልቶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— እናንተ ፡ የሕዝብ ፡
፱ አለቆችና ፡ ሽማግሌዎች ፥ እኛ ፡ ዛሬ ፡ ስለ ድውዩ ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ ተደረገው ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ ይህ ፡
፲ በምን ፡ እንደ ፡ ዳነ ፡ ብንመረመር ፥ እናንተ ፡ በሰቀላችሁት ፡ እግዚአብሔርም ፡ ከሙታን ፡ ባስነሣው ፡ በናዝሬቱ ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ደኅና ፡ ሆኖ ፡ በፊታችሁ ፡ እንደ ፡ ቆመ ፥ ለእናንተ ፡ ለሁላችሁ ፡ ለእስራኤልም ፡ ሕዝብ ፡
፲፩ ሁሉ ፡ የታወቀ ፡ ይሁን ። እናንተ ፡ ግንበኞች ፡ የናቃችሁት ፥ የማዕዘን ፡ ራስ ፡ የሆነው ፡ ይህ ፡
፲፪ ድንጋይ ፡ ነው ። መዳንም ፡ በሌላ ፡ በማንም ፡ የለም ፤ እንድንበት ፡ ዘንድ ፡ የሚገባን ፡ ለሰዎች ፡ የተሰጠ ፡ ስም ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡ ሌላ ፡ የለምና ።
፲፫ ጴጥሮስና ፡ ዮሐንስም ፡ በግልጥ ፡ እንደ ፡ ተናገሩ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፥ መጽሐፍን ፡ የማያውቁና ፡ ያልተማሩ ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ አስተውለው ፡ አደነቁ ፥ ከኢየሱስም ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ አወ
፲፬ ቁአቸው ፤ የተፈወሰውንም ፡ ሰው ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ቆሞ ፡ ሲያዩ ፡ የሚመልሱትን ፡ አጡ ።
፲፭ ከሸንጎም ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ይወጡ ፡ ዘንድ ፡ አዝ
፲፮ ዘው ፡— በእነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ምን ፡ እንሥራ ? የታወቀ ፡ ምልክት ፡ በእነርሱ ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ተደረገ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ተገልጦአልና ፥ እንሸሽገውም ፡ ዘንድ ፡ አንችልም ፤ ነገር ፡
፲፯ ግን ፡ በሕዝቡ ፡ ዘንድ ፡ አብዝቶ ፡ እንዳይስፋፋ ፥ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ለማንም ፡ ሰው ፡ በዚህ ፡ ስም ፡ እንዳይናገሩ ፡ አየዛትን ፡ እንዝዛቸው ፡
፲፰ ብለው ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተማከሩ ። ጠርተውም ፡ በኢየሱስ ፡ ስም ፡ ፈጽመው ፡ እንዳይና
፲፱ ገሩና ፡ እንዳያስተምሩ ፡ አዘዙአቸው ። ጴጥሮስና ፡ ዮሐንስ ፡ ግን ፡ መልሰው ፡— እግዚአብሔርን ፡ ከመስማት ፡ ይልቅ ፡ እናንተን ፡ እንሰማ ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የሚገባ ፡ እንደ ፡
፳ ሆነ ፡ ቍረጡ ፤ እኛስ ፡ ያየነውንና ፡ የሰማነውን ፡ ከመናገር ፡ ዝም ፡ ማለት ፡ አንችልም ፡ አሉአ
፳፩ ቸው ። እነርሱም ፡ እንደ ፡ ምን ፡ እንደሚቀጡ ፡ ምክንያት ፡ ስላላገኙባቸው ፥ እንደ ፡ ገና ፡ ዝተው ፡ ከሕዝቡ ፡ የተነሣ ፡ ፈቱአቸው ፤ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ሆነው ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያከብሩ ፡
፳፪ ነበርና ። ይህ ፡ የመፈወስ ፡ ምልክት ፡ የተደረገለት ፡ ሰው ፡ ከአርባ ፡ ዓመት ፡ ይበልጠው ፡ ነበርና ።
፳፫ ተፈትተውም ፡ ወደ ፡ ወገኖቻቸው ፡ መጡና ፡ የካህናት ፡ አለቆችና ፡ ሽማግሌዎች ፡ ያሉአቸውን ፡

ሮ። ፲፭፤ ዮሐ. ፩፥፬፤፲፯፥፫። ፲፮፤ ማቴ. ፱፥፳፪። ፲፯፤ ሉቃ. ፳፫፥፴፬። ፲፰፤ ሉቃ. ፳፬፥፳፭—፳፯። ፲፱፤ ም. ፪፥፴፰፤ሕገ. ፴፪፥፳፫—፳፯። ፳፪፡፳፫፤ ዘዳግ. ፲፰፥፲፭፡፲፰፡፲፱። ፳፭፤ ዘፍጥ. ፳፪፥፲፰።
፬። ፩፡፪፤ ማቴ. ፳፪፥፳፫። ፫፤ ሉቃ. ፳፩፥፲፪። ፯፤ ዮሐ. ፲፰፥፲፫። ፰፤ ማቴ. ፳፩፥፳፫። ፱፤ ማቴ. ፲፥፲፱። ፲፤ ም. ፫፥፮። ፲፩፤ መዝ. ፻፲፰፥፳፪፤ማቴ. ፳፩፥፵፪። ፲፪፤ ማቴ. ፩፥፳፩። ፲፫፤ ማር. ፫፥፲፬። ፲፬፤ ማቴ. ፲፥፲፱።

፳፬፤ ሁሉ ፡ ነገሩአቸው ። እነርሱም ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ በአንድ ፡ ልብ ፡ ሆነው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ድምፃቸውን ፡ ከፍ ፡ አደረጉ ፡ እንዲህም ፡ አሉ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ሰማዩንና ፡ ምድሩን ፡ በሕሩንም ፡ በእነርሱም ፡ የሚኖረውን ፡ ሁሉ ፡ የፈ
፳፭፤ ጠርህ ፥ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ በብላቴናህ ፡ በአባታችን ፡ በዳዊት ፡ አፍ ፡— አሕዛብ ፡ ስምን ፡ አጕረመረሙ ? ሕዝቡስ ፡ ከንቱን ፡ ነገር ፡ ስምን ፡
፳፮፤ አሰቡ ? የምድር ፡ ነገሥታት ፡ ተነሡ ፡ አለቆችም ፡ በጌታና ፡ በተቀበው ፡ ላይ ፡ አብረው ፡ ተከማቹ ፡ ብሎ ፡ የተናገርህ ፡ አምላክ ፡ ነህ ።
፳፯፡፳፰፤ በቀባኸው ፡ በቅዱሱ ፡ ብላቴናህ ፡ በኢየሱስ ፡ ላይ ፡ ሄሮድስና ፡ ጴንጤናዊው ፡ ጲላጦስ ፡ ከአሕዛብና ፡ ከእስራኤል ፡ ሕዝብ ፡ ጋር ፥ እጅህና ፡ አሳብህ ፡ እንዲሆን ፡ አስቀድመው ፡ የወሰኑትን ፡ ሁሉ ፡ ሊፈጽሙ ፥ በዚች ፡ ከተማ ፡ በእውነት ፡
፳፱፡፴፤ ተሰበሰቡ ። አሁንም ፥ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ ዛቻቸው ፡ ተመልከት ፤ በመፈወስም ፡ እጅህን ፡ ስትዘረጋ ፡ በቅዱስ ፡ ብላቴናህም ፡ በኢየሱስ ፡ ስም ፡ ምልክትና ፡ ድንቅ ፡ ሲደረግ ፥ በሪያዎችህ ፡ በፍጹም ፡ ግልጥነት ፡ ቃልህን ፡ እንዲናገሩ ፡ ስጣ
፴፩፤ ቸው ። ከጸለዩም ፡ በኋላ ፡ ተሰብስበው ፡ የነበሩበት ፡ ስፍራ ፡ ተናወጠ ፥ በሁሉም ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሞላባቸው ፥ የእግዚአብሔርንም ፡ ቃል ፡ በግልጥ ፡ ተናገሩ ።

፴፪፤ ያመኑትም ፡ ሕዝብ ፡ አንድ ፡ ልብ ፡ አንዲትም ፡ ነፍስ ፡ ነበሩአቸው ፥ ገንዘባቸውም ፡ ሁሉ ፡ በአንድነት ፡ ነበረ ፡ እንጂ ፡ ካለው ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ስንኳ ፡ የራሱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ማንም ፡ አልተናገረም ።
፴፫፤ ሐዋርያትም ፡ የጌታን ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ ትንሣኤ ፡ በታላቅ ፡ ኃይል ፡ ይመሰክሩ ፡ ነበር ፤ በሁሉም ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ጸጋ ፡ ነበረበ
፴፬፤ ቸው ። በመካከላቸው ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ ችግረኛ ፡ አልነበረምና ፤ መሬት ፡ ወይም ፡ ቤት ፡ ያላቸው ፡ ሁሉ ፡ እየሸጡ ፡ የተሸጠውን ፡ ዋጋ ፡ ያመጡ ፡
፴፭፤ ነበርና ፥ በሐዋርያትም ፡ እግር ፡ አጠገብ ፡ ያኖሩ ፡ ነበር ፤ ማናቸውም ፡ እንደሚፈልግ ፡ መጠን ፡
፴፮፤ ለእያንዳንዱ ፡ ያካፍሉት ፡ ነበር ። ትውልዱም ፡ የቆጵሮስ ፡ ሰው ፡ የነበረ ፡ አንድ ፡ ሌዋዊ ፡ ዮሴፍ ፡ የሚሉት ፡ ነበረ ፥ እርሱም ፡ በሐዋርያት ፡ በርናባስ ፡ ተባለ ፡ ትርጓሜውም ፡ የመጽናናት ፡ ልጅ ፡
፴፯፤ ነው ፤ እርሻም ፡ ነበረውና ፡ ሸጦ ፡ ገንዘቡን ፡ አምጥቶ ፡ ከሐዋርያት ፡ እግር ፡ አጠገብ ፡ አኖረው ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩፤ ሐናንያም ፡ የተባለ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሰጲራ ፡
፪፤ ከተባለች ፡ ከሚስቱ ፡ ጋር ፡ መሬት ፡ ሸጠ ፥ ሚስቱም ፡ ደግሞ ፡ ስታውቅ ፡ ከሽያጩ ፡ አስቀረና ፡ እኩሌታውን ፡ አምጥቶ ፡ በሐዋርያት ፡ እግር ፡
፫፤ አጠገብ ፡ አኖረው ። ጴጥሮስም ፡— ሐናንያ ፡ ሆይ ፥ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ታታልልና ፡ከመሬቱ ፡ ሽያጭ ፡ ታስቀር ፡ ዘንድ ፡ ሰይጣን ፡ በልብህ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ሞላ ? ሳትሸጠው ፡ የአንተ ፡ አልነ
፬፤ በረምን ? ከሸጥኸውስ ፡ በኋላ ፡ በሥልጣንህ ፡ አልነበረምን ? ይህን ፡ ነገር ፡ ስለ ፡ ምን ፡ በልብህ ፡ አሰብህ ? እግዚአብሔርን ፡ እንጂ ፡ ሰውን ፡ አልዋሸህም ፡ አለው ። ሐናንያም ፡ ይህን ፡
፭፤ ቃል ፡ ሰምቶ ፡ ወድቆ ፡ ሞተም ፤ በሰሙትም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ፍርሃት ፡ ሆነ ። ጕበዛችም ፡
፮፤ ተነሥተው ፡ከፈኑት ፡ አውጥተውም ፡ ቀበሩት ።
፯፤ ከሦስት ፡ ሰዓት ፡ ያህል ፡ በኋላም ፡ ሚስቱ ፡
፰፤ የሆነውን ፡ ሳታውቅ ፡ ገባች ። ጴጥሮስም ፡ መልሶ ፡— እስቲ ፡ ንገሪኝ ፥ መሬታችሁን ፡ ይህን ፡ በሚያህል ፡ሸጣችሁትን ? አላት ። እርስዋም ፡— አዎን ፥ ይህን ፡ በሚያህል ፡ ነው ፡
፱፤ አለች ። ጴጥሮስም ፡— የጌታን ፡ መንፈስ ፡ ትፈታተኑ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ተስማማችሁ ? እነሆ ፥ ባልሽን ፡ የቀበሩት ፡ ሰዎች ፡ እግር ፡ በደጅ ፡ ነው ፡ አንቺንም ፡ ያወጡሻል ፡ አላት ።
፲፤ ያን ፡ ጊዜም ፡ በእግሩ ፡ አጠገብ ፡ ወደቀች ፡ ሞተችም ፤ ጕበዛችም ፡ ሲገቡ ፡ ሞታ ፡ አገኙአት ፡ አውጥተውም ፡ በባልዋ ፡ አጠገብ ፡ ቀበሩአት ።
፲፩፤ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሁሉና ፡ ይህንም ፡ በሰሙ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ፍርሃት ፡ ሆነ ።

፲፪፤ በሐዋርያትም ፡ እጅ ፡ ብዙ ፡ ምልክትና ፡ ድንቅ ፡ በሕዝብ ፡ መካከል ፡ ይደረግ ፡ ነበር ፤ ሁሉም ፡ በአንድ ፡ ልብ ፡ ሆነው ፡ በሰሎሞን ፡
፲፫፤ ደጅ ፡ መመላለሻ ፡ ነበሩ ። ከሌሎችም ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ ሊተባበራቸው ፡ የሚደፍር ፡ አልነበረም ፥
፲፬፤ ሕዝቡ ፡ ግን ፡ ያከብሩአቸው ፡ ነበር ፤ የሚያምኑትም ፡ ከፊት ፡ ይልቅ ፡ በጌታ ፡ ይጨመሩለት ፡ ነበር ፤ ወንዶችና ፡ ሴቶችም ፡ ብዙ ፡ ነበሩ ።
፲፭፤ ስለዚህም ፡ ጴጥሮስ ፡ ሲያልፍ ፡ ጥላውም ፡ ቢሆን ፡ ከእነርሱ ፡ አንዱን ፡ ይጋርድ ፡ ዘንድ ፡ድውያንን ፡ ወደ ፡ አደባባይ ፡ አውጥተው ፡ በአልጋና ፡ በወስካ ፡ ያኖሩአቸው ፡ ነበር ። ደግ
፲፮፤ ሞም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ዙሪያ ፡ካሉችው ፡ ከተማ ፡ ድውያንንና ፡ በርኵሳን ፡ መናፍስት ፡ የተሣቀዩትን ፡ እያመጡ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ይሰበሰቡ ፡ ነበር ፤ ሁሉም ፡ ይፈወሱ ፡ ነበር ።

፲፯፤ ሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ ግን ፡ የሰዱቃውያን ፡ ወገን ፡ ሆነውም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ ሁሉ ፡ ተነሡ ፡
፲፰፤ ቅንዓትም ፡ ሞላባቸው ። በሐዋርያትም ፡ ላይ ፡ እጃቸውን ፡ ጭነው ፡ በሕዝቡ ፡ ወኅኒ ፡ ውስጥ ፡
፲፱፤ አኖሩአቸው ። የጌታ ፡ መልአክ ፡ ግን ፡ በሌሊት ፡ የወኅኒውን ፡ ደጅ ፡ ከፍቶ ፡ አወጣቸውና ፡—
፳፤ ሂዱና ፡ ቆማችሁ ፡ የዚህን ፡ ሕይወት ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ለሕዝብ ፡ በመቅደስ ፡ ንገሩ ፡ አላቸው ።
፳፩፤ በሰሙም ፡ ጊዜ ፡ ማልደው ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ ገብተው ፡ አስተማሩ ።

ግን ፡ ሊቀ ፡ ካህናቱና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የነበሩት ፡ መጥተው ፡ ሸንጎውንና ፡ የእስራኤልን ፡

፬። ፳፬፤ ሀዋሕ ፬፥፳፬። ፳፭፡፳፮፤ መዝ ፪፥፩-፪። ፳፯፤ ምዕ ፪፥፳፫። ፴፪—፴፯፤ ምዕ ፪፥፵፬፡፵፭። ፴፭፤ ሀዋሕ ፲፭፥፲፭።
፭። ፪፤ ምዕ ፬፥፴፬፡፴፭። ፲፪፤ ምዕ ፫፥፲፭። ፲፭፡፲፮፤ ማር ፮፥፶፭፡፶፮፤ ሉቃ ፲፱፥፲፱። ፲፱፤ ምዕ ፰፥፳፯፤ ፲፥፫፤ ፲፪፥፯፤ ፳፮፥፳፫። ፳፤ ዮሐ ፮፥፷፰።

ልጆች ፡ ሽማግሌዎች ፡ ሁሉ ፡ በአንድነት ፡ ጠሩ ÷ ያመጡአቸውም ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ወኅኒ ፡ ላኩ ። ፳፪፥፳፫ ሎሌዎችም ፡ መጥተው ፡ በወኅኒው ፡ አላገኙአቸውም ፤ ተመልሰውም ፡— ወኅኒው ፡ በጣም ፡ በጥንቃቄ ፡ ተዘግቶ ፡ ጠባቂዎችም ፡ በደጁ ፡ ፊት ፡ ቆመው ፡ አገኘን ÷ በከፈትን ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ በውስጡ ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ አላገኘንም ፡ አሉአቸው ። ፳፬ የመቅደስ ፡ አዛዥና ፡ የካህናት ፡ አለቆችም ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡— እንጃ ፡ ይህ ፡ ምን ፡ ይሆን ? እያሉ ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ አመነቱ ። ፳፭ አንድ ፡ ሰውም ፡ መጥቶ ፡— እነሆ ÷ በወኅኒ ፡ ያኖራችኋቸው ፡ ሰዎች ፡ እየቆሙ ፡ ሕዝቡንም ፡ እያስተማሩ ፡ በመቅደስ ፡ ናቸው ፡ ብሎ ፡ ፳፮ አወራላቸው ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አዛዡ ፡ ከሎሌዎች ፡ ጋር ፡ ሄዶ ፡ አመጣቸው ÷ በኃይል ፡ ግን ፡ አይደለም ፤ ሕዝቡ ፡ እንዳይወግሩአቸው ፡ ይፈሩ ፡ ነበርና ።

፳፯ አምጥተውም ፡ በሸንጎ ፡ አቆሙአቸው ። ፳፰ ሊቀ ፡ ካህናቱም ፡— በዚህ ፡ ስም ፡ እንዳታስተምሩ ፡ አጥብቀን ፡ አላዘዝናችሁምን ? እነሆም ÷ ኢየሩሳሌምን ፡ በትምህርታችሁ ፡ ሞልታችኋል ፤ የዚያንም ፡ ሰው ፡ ደም ፡ በእኛ ፡ ታመጡብን ፡ ዘንድ ፡ ታስባላችሁ ፡ ብሎ ፡ ጠየቃቸው ። ፳፱ ጴጥሮስና ፡ ሐዋርያትም ፡ መልሰው ፡ አሉ ፡— ከሰው ፡ ይልቅ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ልንታዘዝ ፡ ፴ ይገባል ። እናንተ ፡ በእንጨት ፡ ላይ ፡ ሰቅላችሁ ፡ የገደላችሁትን ፡ ኢየሱስን ፡ የአባቶቻችን ፡ አም ፴፩ ላክ ፡ አስነሣው ፤ ይህን ፡ እግዚአብሔር ÷ ለእስራኤል ፡ ንስሐን ፡ የኃጢአትንም ፡ ስርየት ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ÷ ራስም ፡ መድኃኒትም ፡ አድርጎ ፡ በቀኙ ፡ ፴፪ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገው ። እኛም ፡ ለዚህ ፡ ነገር ፡ ምስክሮች ፡ ነን ÷ ደግሞም ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሚታዘዙት ፡ የሰጠው ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ምስክር ፡ ነው ።

፴፫ እነርሱም ፡ ሲሰሙ ፡ በጣም ፡ ተቈጡ ፡ ሊገድ ፴፬ ሉአቸውም ፡ አሰቡ ። ነገር ፡ ግን ፡ በሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ የከበረ ፡ የሕግ ፡ መምህር ፡ ገማልያል ፡ የሚሉት ፡ አንድ ፡ ፈሪሳዊ ፡ በሸንጎ ፡ ተነሥቶ ፡ ሐዋርያትን ፡ጥቂት ፡ ፈቀቅ ፡ እንዲያደ ፴፭ ርጉአቸው ፡ አዘዘ ÷ እንዲህም ፡ አላቸው ፡— የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ÷ ስለ ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ምን ፡ እንደምታደርጉ ፡ ለራሳችሁ ፡ ተጠንቀቁ ። ፴፮ ከዚህ ፡ ወራት ፡ አስቀድሞ ፡ ቴዎዳስ ፡— እኔ ፡ ታላቅ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ ተነሥቶ ፡ ነበርና ÷ አራት ፡ መቶ ፡ የሚያህሉ ፡ ሰዎችም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተባበሩ ፤ እርሱም ፡ ጠፋ ፡ የሰሙትም ፡ ሁሉ ፡ ፴፯ ተበተኑ ፡ እንደ ፡ ምናምንም ፡ ሆኑ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሰዎች ፡ በተጻፉበት ፡ ዘመን ፡ የገሊላው ፡ ይሁዳ ፡ ተነሣ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችንም ፡ አሸፍቶ ፡ አስ ከተለ ፤ እርሱም ፡ ጠፋ ፡ የሰሙትም ፡ ሁሉ ፡ ተበ ፴፰ ታተኑ ። አሁንም ፡ እላችኋለሁ ፡— ከእነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ተለዩ ፡ ተዉአቸውም ፤ ይህ ፡ አሳብ ፡ ወይም ፡ ይህ ፡ ሥራ ፡ ከሰው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይጠ ፴፱ ፋልና ፤ ከእግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ ታጠፉአቸው ፡ ዘንድ ፡ አይቻላችሁም ÷ በእርግጥ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ ስትጣሉ ፡ ምናልባት ፡ እንዳትገኙ ።

፵ ሰሙትም ÷ ሐዋርያትንም ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ጠርተው ፡ ገረፉአቸው ÷ በኢየሱስም ፡ ስም ፡ ፵፩ እንዳይናገሩ ፡ አዝዘው ፡ ፈቱአቸው ። እነር ሱም ፡ ስለ ፡ ስሙ ፡ ይናቁ ፡ ዘንድ ፡ የተገባቸው ፡ ሆነው ፡ ስለ ፡ተቈጠሩ ፡ ከሸንጎው ፡ ፊት ፡ ደስ ፡ ፵፪ እያላቸው ፡ ወጡ ፤ ዕለት ፡ ዕለትም ፡ በመቅደ ስና ፡ በቤታቸው ፡ ስለ ፡ ኢየሱስ ፡ እርሱ ፡ ክር ስቶስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ማስተማርንና ፡ መስበክን ፡ አይተዉም ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ በዚህም ፡ ወራት ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ እየ በዙ ፡ ሲሄዱ ፡ ከግሪክ ፡ አገር ፡ መጥተው ፡ የነበ ሩት ፡ አይሁድ ፡ በይሁዳ ፡ ኖረው ፡ በነበሩት ፡ አይሁድ ፡ አንጐራጐሩባቸው ÷ በየቀኑ ፡ በተሠ ራው ፡ አገልግሎት ፡ መበለቶቻቸውን ፡ ችላ ፡ ፪ ይሉባቸው ፡ ነበርና ። አሥራ ፡ ሁለቱም ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ሁሉን ፡ ጠርተው ፡ እንዲህ ፡ አሉ አቸው ፡— የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ትተን ፡ ማዕድን ፡ እናገለግል ፡ ዘንድ ፡ የሚገባ ፡ ነገር ፡ ፫ አይደለም ። ወንድሞች ፡ ሆይ ÷ በመልካም ፡ የተመሰከረላቸውን ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስና ፡ ጥበ ብም ፡ የሞላባቸውን ፡ ሰባት ፡ ሰዎች ፡ ከእናንተ ፡ ምረጡ ÷ ለዚህም ፡ ጉዳይ ፡ እንሾማቸዋለን ፤ ፬ እኛ ፡ ግን ፡ ለጸሎትና ፡ ቃሉን ፡ ለማገልገል ፡ እን ፭ ተጋለን ። ይህም ፡ ቃል ፡ ሕዝብን ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ አሰኛቸው ፤ እምነትና ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ የሞ ላበትን ፡ ሰው ፡ እስጢፋኖስን ፡ ፊልጶስንም ፡ ጵሮ ኮሮስንም ፡ ኒቃሮናንም ፡ ጢሞናንም ፡ ጳርሜና ንም ፡ ወደ ፡ ይሁዲነት ፡ ገብቶ ፡ የነበረውን ፡ የአ ፮ ንጾኪያውን ፡ ኒቆላዎስንም ፡ መረጡ ። በሐዋር ያትም ፡ ፊት ፡ አቆሙአቸው ÷ ከጸለዩም ፡ በኋላ ፡ እጃቸውን ፡ ጫኑባቸው ።

፯ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ እየሰፋ ፡ ሄደ ÷ በኢየሩሳሌምም ፡ የደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ቍጥር ፡ እጅግ ፡ እየበዛ ፡ ሄደ ፤ ከካህናትም ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ለሃይማኖት ፡ የታዘዙ ፡ ሆኑ ።

፰ እስጢፋኖስም ፡ ጸጋንና ፡ ኃይልን ፡ ተሞልቶ ፡ በሕዝቡ ፡ መካከል ፡ ድንቅንና ፡ ታላቅ ፡ ምል ፱ ክትን ፡ ያደርግ ፡ ነበር ። የነጻ ፡ ወጪዎች ፡ ከተ ባሉቸው ፡ ምኩራብም ፡ ከቀሬናና ፡ ከእስክንድር ያም ፡ ሰዎች ፡ ከኪልቅያና ፡ ከእስያም ፡ ከነበሩት ፡ እንዳንዶቹ ፡ ተነሥተው ፡ እስጢፋኖስን ፡ ይከራ ፲ ከሩት ፡ ነበር ፤ ይናገርበት ፡ የነበረውንም ፡ ጥበ ብና ፡ መንፈስ ፡ ይቃወሙ ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉም ።

፭። ፳፪፤ ምዕ. ፲፪ ÷ ፲፰። ፳፰፤ ምዕ. ፬ ÷ ፲፰ ፤ ማቴ. ፳፯ ÷ ፳፭። ፳፱፤ ሥራ. ፬ ÷ ፲፱—፳። ፴—፴፩፤ ምዕ. ፪ ÷ ፴፪ ፡ ፴፫ ፡ ፴፮።
፴፪፤ ማቴ. ፲፭ ÷ ፳፫። ፴፬፤ ምዕ. ፳፪ ÷ ፫። ፵፤ ምዕ. ፬ ÷ ፲፰ ፤ ማቴ. ፲ ÷ ፲፯። ፵፩፤ ማቴ. ፭ ÷ ፲፩ ፡ ፲፪።
፮። ፩፤ ምዕ. ፬ ÷ ፴፭። ፫፤ ምዕ. ፲፫ ÷ ፪። ፲፤ ሉቃ. ፳፩ ÷ ፲፭።

፲፩ በዚያን ፡ ጊዜ — በሙሴ ፡ ላይ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ላይ ፡ የስድብን ፡ ነገር ፡ ሲናገር ፡ ሰምተነዋል ፡ የሚሉ ፡ ሰዎችን ፡ አስነሡ ። ፲፪ ሕዝቡንና ፡ ሽማግሌዎችንም ፡ ጻፎችንም ፡ አናደዱ ፤ ቀርበውም ፡ ያዙት ፡ ወደ ፡ ሸንጎም ፡ አመጡትና ፡— ፲፫ ይህ ፡ ሰው ፡ በዚህ ፡ በተቀደሰው ፡ ስፍራ ፡ በሕግም ፡ ላይ ፡ የስድብን ፡ ነገር ፡ ለመናገር ፡ አይተውም ፤ ፲፬ ይህ ፡ የናዝሬቱ ፡ ኢየሱስ ፡ ይህን ፡ ስፍራ ፡ ያፈርሰዋል ፡ ሙሴም ፡ ያስተላለፈልንን ፡ ሥርዓት ፡ ይለውጣል ፡ ሲል ፡ ሰምተነዋልና ፡ የሚሉ ፡ የሐሰት ፡ ምስክሮችን ፡ አቆሙ ። ፲፭ በሸንጎም ፡ የተቀመጡት ፡ ሁሉ ፡ ትኵር ፡ ብለው ፡ ሲመለከቱት ፡ እንደ ፡ መልአክ ፡ ፊት ፡ ሆኖ ፡ ፊቱን ፡ አዩት ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ሊቀ ፡ ካህናቱም ፡— ይህ ፡ ነገር ፡ እንዲህ ፡ ነውን ? አለው ፤ ፪ እርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ወንድሞችና ፡ አባቶች ፡ ሆይ ፥ ስሙ ። የክብር ፡ አምላክ ፡ ለአባታችን ፡ ለአብርሃም ፡ በካራን ፡ ሳይቀመጥ ፡ ገና ፡ በሁለት ፡ ወንዝ ፡ መካከል ፡ ሳለ ፡ ታየና ፡— ፫ ከአገርህና ፡ ከዘመዶችህም ፡ ወጥተህ ፡ ወደማሳይህ ፡ ወደ ፡ ማንኛውም ፡ ምድር ፡ ና ፡ አለው ። ፬ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከከለዳውያን ፡ አገር ፡ ወጥቶ ፡ በካራን ፡ ተቀመጠ ። ከዚያም ፡ አባቱ ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ እናንተ ፡ ዛሬ ፡ ወደምትኖሩበት ፡ ፭ ወደዚች ፡ አገር ፡ አወጣው ። በዚችም ፡ የእግር ፡ ጫማ ፡ ስንኳ ፡ የሚያህል ፡ ርስት ፡ አልሰጠውም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ልጅ ፡ ሳይኖረው ፡ ለእርሱ ፡ ከእርሱም ፡ በኋላ ፡ ለዘሩ ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ ይሰጠው ፡ ፮ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ ሰጠው ። እግዚአብሔርም ፡ ዘሩ ፡ በሌላ ፡ አገር ፡ መጻተኞች ፡ እንዲሆኑ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ዓመትም ፡ ባሪያዎች ፡ እንዲያደርጉአቸው ፡ እንዲያስጨንቁአቸውም ፡ እንዲህ ፡ ተናገረ ፤ ፯ ደግሞም ፡ እግዚአብሔር ፡— እንደ ፡ ባሪያዎች ፡ በሚገዙአቸው ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ እኔ ፡ እፈርድባቸዋለሁ ፥ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ይወጣሉ ፡ ፰ በዚህም ፡ ስፍራ ፡ ያመልኩኛል ፡ አለ ። የመገረዝንም ፡ ኪዳን ፡ ሰጠው ፤ እንዲሁም ፡ ይስሐቅን ፡ ወለደ ፡ በስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ ገረዘው ፡ ይስሐቅም ፡ ያዕቆብን ፡ ያዕቆብም ፡ አሥራ ፡ ሁለቱን ፡ የአባቶችን ፡ አለቆች ።

፱ የአባቶችም ፡ አለቆች ፡ በዮሴፍ ፡ ቀንተው ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ሸጡት ፤ እግዚአብሔርም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፥ ፲ ከመከራውም ፡ ሁሉ ፡ አወጣው ፥ በግብፅ ፡ ንጉሥ ፡ በፈርዖንም ፡ ፊት ፡ ሞገስንና ፡ ጥበብን ፡ ሰጠው ፥ በግብፅና ፡ በቤቱ ፡ ሁሉ ፡ ላይም ፡ ቢትወደድ ፡ አድርጎ ፡ ሾመው ። ፲፩ በግብፅና ፡ በከነዓንም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ራብና ፡ ብዙ ፡ ጭንቅ ፡ መጣ ፥ አባቶቻችንም ፡ ምግብን ፡ አላገኙም ። ፲፪ ያዕቆብም ፡ በግብፅ ፡ እህል ፡ መኖሩን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ በመጀመሪያ ፡ አባቶቻችንን ፡ ላደዳቸው ፤ ፲፫ በሁለተኛውም ፡ ዮሴፍ ፡ ለወንድሞቹ ፡ ታወቀ ፥ የዮሴፍም ፡ ትውልድ ፡ በፈርዖን ፡ ዘንድ ፡ ተገለጠ ። ፲፬ ዮሴፍም ፡ አባቱን ፡ ያዕቆብንና ፡ ሰባ ፡ አምስት ፡ነፍስ ፡ የነበረውን ፡ ቤተ ፡ ዘመድ ፡ ሁሉ ፡ ልኮ ፡ አስጠራ ። ፲፭ ያዕቆብም ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ወረደ ፡ እርሱም ፡ሞተ ፡ አባቶቻችንም ፤ ፲፮ ወደ ፡ሴኬምም ፡ አፍልሰው ፡ አብርሃም ፡ ከሴኬም ፡ አባት ፡ ከኤሞር ፡ ልጆች ፡ በብር ፡ በገዛው ፡ መቃብር ፡ ቀበሩአቸው ።

፲፯፡፲፰ እግዚአብሔርም ፡ ለአብርሃም ፡ የማለለት ፡ የተስፋው ፡ ዘመን ፡ ሲቀርብ ፥ ዮሴፍን ፡ የማያውቀው ፡ ሌላ ፡ ንጉሥ ፡ በግብፅ ፡ ላይ ፡ እስኪነሣ ፡ ድረስ ፥ ሕዝቡ ፡ እየተጨመሩ ፡ በግብፅ ፡ በዙ ። ፲፱ እርሱም ፡ ወገናችንን ፡ ተተንኰሎ ፡ ሕፃናትን ፡ በሕይወት ፡ እንዳይጠብቁ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ይጥሉ ፡ ዘንድ ፡ አድርጎ ፡ አባቶቻችንን ፡ አስጨነቀ ። ፳ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሙሴ ፡ ተወለደ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ያማረ ፡ ነበር ፤ በአባቱ ፡ ቤትም ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ አደገ ፤ ፳፩ በተጣለም ፡ ጊዜ ፡ የፈርዖን ፡ ልጅ ፡ አነሣችው ፡ ልጅም ፡ ይሆናት ፡ ዘንድ ፡ አሳደገችው ። ፳፪ ሙሴም ፡ የግብፆችን ፡ ጥበብ ፡ ሁሉ ፡ ተማረ ፥ በቃሉና ፡ በሥራውም ፡ የበረታ ፡ ሆነ ።

፳፫ ነገር ፡ ግን ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ሲሞላው ፡ ወንድሞቹን ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ይጐበኝ ፡ ዘንድ ፡ በልቡ ፡ አሰበ ። ፳፬ አንዱም ፡ ሲበደል ፡ አይቶ ፡ ረዳው ፥ የግብፅን ፡ ሰውም ፡ መትቶ ፡ ስለተገፋው ፡ ተበቀለ ። ፳፭ ወንድሞቹም ፡ እግዚአብሔር ፡ በእጁ ፡ መዳንን ፡ እንዲሰጣቸው ፡ የሚያስተውሉ ፡ ይመስለው ፡ ነበር ፥ እነርሱ ፡ ግን ፡ አላስተዋሉም ። ፳፮ በማግሥቱም ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ሲጣሉ ፡ አገኛቸው ፥ ሊያስታርቃቸውም ፡ ወዶ ፡— ሰዎች ፡ ሆይ ፥ እናንተስ ፡ ወንድማማች ፡ ናችሁ ፤ ስለ ፡ ምን ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ትበዳደላላችሁ ? አላቸው ። ፳፯ ያም ፡ባልንጀራውን ፡ የሚበድል ፡ግን ፡— አንተን ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ ሹምና ፡ ፈራጅ ፡ አንድትሆን ፡ የሾመህ ፡ ማን ፡ ነው ? ፳፰ ወይስ ፡ ትናንትና ፡ የግብፁን ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ገደልኸው ፡ ልትገድለኝ ፡ ትወዳለህን ? ብሎ ፡ገፋው ። ፳፱ ሙሴም ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ የተነሣ ፡ ሸሽቶ ፡ በምድያም ፡ አገር ፡ መጻተኛ ፡ ሆኖ ፡ኖረ ፤ በዚያም ፡ ሁለት ፡ ልጆች ፡ ወለደ ።

፴ አርባ ፡ ዓመትም ፡ ሲሞላ ፡ የጌታ ፡ መልአክ ፡ በሲና ፡ ተራራ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በቍጥቋጦ ፡ መካከል ፡ በእሳት ፡ ነበልባል ፡ ታየው ። ፴፩፡፴፪ ሙሴም ፡ አይቶ ፡ በየው ፡ ተደነቀ ፤ ሊመለከትም ፡ ሲቀ

፮ ። [illegible]

፯ ። [illegible]

ርብ ፡ የጌታ ፡ ቃል ፥— እኔ ፡ የአባቶችህ ፡ አም ላክ ፡ የአብርሃም ፡ አምላክ ፡ የይስሐቅም ፡ አም ላክ ፡ የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጣ ። ሙሴም ፡ ተንቀጥቀጠ ፡ ሊመለ
፴፫ ከት ፡ አልደፈረም ። ጌታም ፥— የቆምህበት ፡ ስፍራ ፡ የተቀደሰች ፡ ምድር ፡ ናትና ፡ የእግርህን ፡
፴፬ ጫማ ፡ አውልቅ ። በግብፅ ፡ ያሉትን ፡ የሕዝ ቤን ፡ መከራ ፡ ፈጽሜ ፡ አይቼ ፡ መቃተታቸው ንም ፡ ሰምቼ ፡ ላድናቸው ፡ ወረድሁ ፤ አሁንም ፡ ና ፥ ወደ ፡ ግብፅ ፡ እልክሃለሁ ፡ አለው ።
፴፭ ሹምና ፡ ፈራጅ ፡ እንድትሆን ፡ የሾመህ ፡ ማን ፡ ነው ? ብለው ፡ የካዱትን ፥ ይህን ፡ ሙሴን ፡ በቍ ጥቋጦው ፡ በታየው ፡ በመልአኩ ፡ እጅ ፡ እግዚአ
፴፮ ብሔር ፡ ሹምና ፡ ቤዛ ፡ አድርጎ ፡ላከው ። ይህ ፡ ሰው ፡ በግብፅ ፡ ምድርና ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ በምድረ ፡ በዳም ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ድንቅና ፡ ምል
፴፯ ክት ፡ እያደረገ ፡ አወጣቸው ። ይህ ፡ ሰው ፡ ለእ ስራኤል ፡ ልጆች ፥— እግዚአብሔር ፡ ከወንድ ሞቻችሁ ፡ እንደ ፡ እኔ ፡ ያለ ፡ ነቢይ ፡ ያስነሣላች ኋል ፤ እርሱን ፡ ስሙት ፡ ያላቸው ፡ ሙሴ ፡ ነው ።
፴፰ ይህ ፡ ሰው ፡ በሲና ፡ ተራራ ፡ ከተናገረው ፡ መል አክና ፡ ከአባቶቻችን ፡ ጋር ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ በማ ኅበሩ ፡ ውስጥ ፡ የነበረው ፡ ነው ፤ ይሰጠንም ፡ ዘንድ ፡ ሕይወት ፡ ያላቸውን ፡ ቃላት ፡ ተቀበለ ፤
፴፱ ለእርሱም ፡ አባቶቻችን ፡ ሊታዘዙት ፡ አልወደ ዱም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ገፉት ፡ በልባቸውም ፡ ወደ ፡
፵ ግብፅ ፡ ተመለሱ ፤ አሮንንም ፥— በፊታችን ፡ የሚሄዱ ፡ አማልክት ፡ ሥራልን ፤ ይህ ፡ ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣን ፡ ሙሴ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
፵፩ አናውቅምና ፡ አሉት ። በዚያም ፡ ወራት ፡ ጥጃ ፡ አደረጉ ፡ ለጣዖቱም ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረቡ ፥
፵፪ በእጃቸውም ፡ ሥራ ፡ ደስ ፡ አላቸው ። እግዚአብ ሔር ፡ ግን ፡ ዘወር ፡ አለ ፡ የሰማይንም ፡ ጭፍራ ፡ ያመልኩ ፡ ዘንድ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፥ በነቢያ ትም ፡ መጽሐፍ ፡—እናንተ ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፥ አርባ ፡ ዓመት ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የታረደውን ፡ ከብ
፵፫ ትና ፡ መሥዋዕትን ፡ አቀረባችሁልኝን ? ትሰ ግዱላቸውም ፡ ዘንድ ፡ የሠራችኋቸውን ፡ ምስ ሎች ፡ እነርሱንም ፡ የሞሎክን ፡ ድንኳንና ፡ ሬም ፋም ፡ የሚሉትን ፡ የአምላካችሁን ፡ ኮከብ ፡ አነ ሣችሁ ፤ እኔም ፡ ከባቢሎን ፡ወዲያ ፡ አስለቅቃችኋ ለሁ ፡ ተብሎ ፡ እንዲህ ፡ ተጽፎአል ።
፵፬ እንዳየው ፡ ምስል ፡ አድርጎ ፡ ይሠራት ፡ ዘንድ ፡ ሙሴን ፡ ተናግሮ ፡ እንዳዘዘው ፥ የምስክር ፡ ድን ኳን ፡ ከአባቶቻችን ፡ ዘንድ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ነበ
፵፭ ረች ፤ አባቶቻችንም ፡ ደግሞ ፡ በተራ ፡ ተቀ ብለው ፡ እግዚአብሔር ፡ በፊታቸው ፡ ያወጣቸ ውን ፡ የአሕዛብን ፡ አገር ፡ በያዙት ፡ ጊዜ ፡ ከኢ ያሱ ፡ ጋር ፡ አገቡአት ፥ እስከ ፡ ዳዊት ፡ዘመንም ፡
፵፮ ድረስ ፡ኖረች ። እርሱም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ሞገስ ፡ አግኝቶ ፡ ለያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ማደ
፵፯ ሪያን ፡ ያገኝ ፡ ዘንድ ፡ለመነ ። ነገር ፡ ግን ፡ ሰሎ
፵፰ ፡ ፵፱ ሞን ፡ ቤት ፡ ሠራለት ። ነገር ፡ ግን ፡ ነቢዩ ፥— ሰማይ ፡ ዙፋኔ ፡ ነው ፡ ምድርም ፡ የእግሬ ፡ መረ ገጫ ፡ ናት ፤ ለእኔ ፡ ምን ፡ ዓይነት ፡ ቤት ፡ ትሠራ ላችሁ ? ይላል ፡ ጌታ ፥ ወይስ ፡ የማርፍበት ፡ ስፍራ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ይህንስ ፡ ሁሉ ፡ እጄ ፡ የሠራችው ፡ አይደለምን ? እንዳለ ፥ ልዑል ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ በሠራችው ፡ አይኖርም ።
፶፩ እናንተ ፡ አንገተ ፡ ደንዳኖች ፡ልባችሁና ፡ ጆሮ አችሁም ፡ያልተገረዘ ፥እናንተ ፡ ሁልጊዜ ፡ መን ፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ትቃወማላችሁ ፤ አባቶቻችሁ ፡
፶፪ ፡ ፶፫ እንደ ፡ ተቃወሙት ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ። ከነቢያ ትስ ፡ አባቶቻችሁ ፡ ያላሳደዱት ፡ ማን ፡ ነው ? የጻድቁንም ፡ መምጣት ፡ አስቀድሞ ፡ የተናገሩ ትን ፡ ገደሉአቸው ፤ በመላእክት ፡ ሥርዓት ፡ ሕግን ፡ ተቀብላችሁ ፡ ያልጠበቃችሁት ፡ እናን ተም ፡ አሁን ፡ እርሱን ፡ አሳልፋችሁ ፡ ሰጣች ሁት ፡ ገደላችሁትም ።
፶፬ ይህንም ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ በልባቸው ፡ በጣም ፡
፶፭ ተቈጡ ፡ ጥርሳቸውንም ፡ አፋጩበት ። መን ፈስ ፡ ቅዱስንም ፡ ተሞልቶ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ትኵር ፡ ብሎ ፡ ሲመለከት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ክብር ፡ ኢየሱስንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ቆሞ ፡
፶፮ አየና ፥— እነሆ ፥ ሰማያት ፡ ተከፍተው ፡ የሰው ፡ ልጅም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ቆሞ ፡ አያለሁ ፡
፶፯ አለ ። በታላቅ ፡ ድምፅም ፡ እየጮኹ ፡ ጆሮአቸ ውን ፡ ደፈኑ ፥ በአንድ ፡ ልብ ፡ ሆነውም ፡ ወደ ፡
፶፰ እርሱ ፡ሮጡ ፥ ከከተማም ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አውጥ ተው ፡ ወገሩት ። ምስክሮችም ፡ ልብሳቸውን ፡ ሳውል ፡ በሚሉት ፡ በአንድ ፡ ጎበዝ ፡ እግር ፡ አጠ
፶፱ ገብ ፡ አኖሩ ። እስጢፋኖስም ፥— ጌታ ፡ ኢየሱስ ፡ ሆይ ፥ ነፍሴን ፡ተቀበል ፡ ብሎ ፡ ሲጠራ ፡ ይወግ
፷ ሩት ፡ ነበር ። ተንበርክኮም ፥— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ ኃጢአት ፡ አትቍጠርባቸው ፡ ብሎ ፡ በታ ላቅ ፡ ድምፅ ፡ ጮኸ ። ይህንም ፡ ብሎ ፡ አንቀ ላፋ ። ሳውልም ፡ በእርሱ ፡ መገደል ፡ ተስማ ምቶ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ በዚያን ፡ ቀንም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ባለች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ስደት ፡ ሆነ ፤ ሁሉም ፡ ከሐዋርያትም ፡ በቀር ፡ ወደ ፡ ይሁዳና ፡ ወደ ፡
፪ ሰማርያ ፡ አገሮች ፡ ተበተኑ ። በጸሎትም ፡ የተጉ ፡ ሰዎች ፡ እስጢፋኖስን ፡ ቀበሩት ፡ ታላቅ ፡ ልቅ
፫ ሶም ፡ አለቀሱለት ። ሳውል ፡ ግን ፡ ቤተ ፡ ክርስ

፯። [illegible]

ቲያንን ፡ ያፈርስ ፡ ነበር ፤ ወደ ፡ ሁሉም ፡ ቤት ፡ እየገባ ፡ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ እየጐተተ ፡ ወደ ፡ ወኅኒ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጥ ፡ ነበር ።

፬ የተበተኑትም ፡ ቃሉን ፡ እየሰበኩ ፡ ዞሩ ። ፭ ፊልጶስም ፡ ወደ ፡ ሰማርያ ፡ ከተማ ፡ ወርዶ ፡ ክርስቶስን ፡ ሰበከላቸው ። ፮ ሕዝቡም ፡ የፊልጶስን ፡ ቃል ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ያደርጋት ፡ የነበረውንም ፡ ምልክት ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፥ የተናገረውን ፡ በአንድ ፡ ልብ ፡ አደመጡ ። ፯ ርኩሳን ፡ መናፍስት ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ እየጮኹ ፡ ከብዙ ፡ ሰዎች ፡ ይወጡ ፡ ነበርና ፤ ብዙም ፡ ሽባዎችና ፡ አንካሶች ፡ ተፈወሱ ፤ ፰ በዚያችም ፡ ከተማ ፡ ታላቅ ፡ ደስታ ፡ ሆነ ።

፱ ሲሞን ፡ የሚሉት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ግን ፡— እኔ ፡ ታላቅ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፥ እየጠንቈለ ፡ የሰማርያንም ፡ ወገን ፡ እያስገረመ ፡ ቀድሞ ፡ በከተማ ፡ ነበረ ። ፲ ከታናናሾችም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታላላቆቹ ፡ ድረስ ፡— ታላቁ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ኃይል ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ፲፩ እያሉ ፡ ሁሉ ፡ ያደምጡት ፡ ነበር ። ከብዙ ፡ ዘመንም ፡ ጀምሮ ፡ በጥንቈላ ፡ ስላስገረማቸው ፡ ያደ ፲፪ ምጡት ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥትና ፡ ስለ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስም ፡ እየሰበከላቸው ፡ ፊልጶስን ፡ ባመኑት ፡ ጊዜ ፥ ፲፫ ወንዶችም ፡ ሴቶችም ፡ ተጠመቁ ። ሲሞንም ፡ ደግሞ ፡ ራሱ ፡ አመነ ፤ ተጠምቆም ፡ ከፊልጶስ ፡ ጋር ፡ ይተባበር ፡ ነበር ፤ የሚደረገውንም ፡ ምልክትና ፡ ታላቅ ፡ ተአምራት ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ተገረመ ።

፲፬ በኢየሩሳሌምም ፡ የነበሩት ፡ ሐዋርያት ፡ የሰማርያ ፡ ሰዎች ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ እንደ ፡ ተቀበሉ ፡ ሰምተው ፡ ጴጥሮስንና ፡ ዮሐንስን ፡ ፲፭ ሰደዱላቸው ። እነርሱም ፡ በወረዱ ፡ ጊዜ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ይቀበሉ ፡ ዘንድ ፡ ጸለዩላቸው ፤ ፲፮ በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ ስም ፡ ብቻ ፡ ተጠምቀው ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ከእነርሱ ፡ በአንዱ ፡ ሳይ ፡ ስንኳ ፡ ፲፯ ገና ፡ አልወረደም ፡ ነበርና ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እጃቸውን ፡ ጫኑባቸው ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስንም ፡ ተቀ ፲፰ በሉ ። ሲሞንም ፡ በሐዋርያት ፡ እጅ ፡ መጫን ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ እንዲሰጥ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፥ ገንዘብ ፡ ፲፱ አመጣላቸውና ፡— እጄን ፡ የምጭንበት ፡ ሁሉ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ይቀበል ፡ ዘንድ ፡ ለእኔ ፡ ፳ ደግሞ ፡ ይህን ፡ ሥልጣን ፡ ስጡኝ ፡ አለ ። ጴጥሮስ ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡— የእግዚአብሔርን ፡ ስጦታ ፡ በገንዘብ ፡ እንድታገኝ ፡ አስበሃልና ፡ ፳፩ ብርህ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ይጥፋ ። ልብህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የቀና ፡ አይደለምና ፡ ከዚህ ፡ ፳፪ ነገር ፡ ዕድል ፡ ወይም ፡ ፈንታ ፡ የለህም ። እንግዲህ ፡ ስለዚህ ፡ ከፋትህ ፡ ንስሐ ፡ ግባ ፥ ምናልባትም ፡ የልብህን ፡ አሳብ ፡ ይቅር ፡ ይልህ ፡ እንደ ፡ ፳፫ ሆነ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለምን ፤ በመራራ ፡ መርዝና ፡ በዓመፅ ፡ እስራት ፡ እንዳለህ ፡ አይሃለ ፳፬ ሁና ። ሲሞንም ፡ መልሶ ፡— ከላችሁት ፡ አን ዳች ፡ እንዳይደርስብኝ ፡ እናንተው ፡ ወደ ፡ ጌታ ፡ ለምኑልኝ ፡ አላቸው ።

፳፭ እነርሱም ፡ ከመሰከሩና ፡ የጌታን ፡ ቃል ፡ ከተናገሩ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ፤ በሰምራውያን ፡ በብዙ ፡ መንደሮችም ፡ ወንጌልን ፡ ሰበኩ ።

፳፮ የጌታም ፡ መልአክ ፡ ፊልጶስን ፡— ተነሥተህ ፡ በደቡብ ፡ በኩል ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ጋዛ ፡ ወደሚያወርደው ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ መን ፳፯ ገድ ፡ ሂድ ፡ አለው ። ተነሥቶም ፡ ሄደ ። እነ ሆም ፥ ህንደኬ ፡ የተባለች ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንግሥት ፡ አዛዥና ፡ ጃንደረባ ፡ የነበረ ፡ በገንዘብ ዋም ፡ ሁሉ ፡ የሠለጠነ ፡ አንድ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰው ፡ ሊሰግድ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጥቶ ፡ ፳፰ ነበር ፤ ሲመለስም ፡ በሰረገላ ፡ ተቀምጦ ፡ የነቢዩን ፡ የኢሳይያስን ፡ መጽሐፍ ፡ ያነብ ፡ ነበር ። ፳፱ መንፈስም ፡ ፊልጶስን ፡— ወደዚህ ፡ ሰረገላ ፡ ቅረ ፴ ብና ፡ ተገናኝ ፡ አለው ። ፊልጶስም ፡ ሮጦ ፡ የነቢዩን ፡ የኢሳይያስን ፡ መጽሐፍ ፡ ሲያነብ ፡ ሰማና ፡— በእውኑ ፡ የምታነበውን ፡ ታስተውለዋለህን ? ፴፩ አለው ። እርሱም ፡— የሚመራኝ ፡ ሳይኖር ፡ ይህ ፡ እንዴት ፡ ይቻለኛል ? አለው ። ወጥቶም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይቀመጥ ፡ ዘንድ ፡ ፊልጶስን ፡ ፴፪ ለመነው ። ያነበውም ፡ የነበረ ፡ የመጽሐፉ ፡ ክፍል ፡ ይህ ፡ ነበረ ፤

እንደ ፡ በግ ፡ ወደ ፡ መታረድ ፡ ተነዳ ፥ የበግ ፡
ጠቦትም ፡ በሸላቹ ፡ ፊት ፡ ዝም ፡ እንደሚል ፥
፴፫ እንዲሁ ፡ አፉን ፡ አልከፈተም ። በውርደቱ ፡ ፍርዱ ፡ ተወገደ ፤ ሕይወቱ ፡ ከም
ድር ፡ ተወግዳለችና ፡ ትውልዱንስ ፡ ማን ፡
ይናገራል ?

፴፬ ጃንደረባውም ፡ ለፊልጶስ ፡ መልሶ ፡— እባክህ ፥ ነቢዩ ፡ ይህን ፡ ስለ ፡ ማን ፡ ይናገራል ? ስለ ፡ ራሱ ፡ ፴፭ ነውን ፡ ወይስ ፡ ስለ ፡ ሌላ ? አለው ። ፊልጶስም ፡ አፉን ፡ ከፈተ ፥ ከዚህም ፡ መጽሐፍ ፡ ጀምሮ ፡ ፴፮ ስለ ፡ ኢየሱስ ፡ ወንጌልን ፡ ሰበከለት ። በመንገድም ፡ ሲሄዱ ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ደረሱ ፤ ጃንደረባውም ፡— እነሆ ፡ ውኃ ፤ እንዳልጠመቅ ፡ የሚከለ ፴፯ ክለኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ? አለው ። ፊልጶስም ፡— በፍጹም ፡ ልብህ ፡ ብታምን ፥ ተፈቅዶአል ፡ አለው ። መልሶም ፡— ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አምናለሁ ፡ ፴፰ አለ ። ሰረገላውም ፡ ይቆም ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፥ ፊልጶስና ፡ ጃንደረባው ፡ ሁለቱም ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ፴፱ ወረዱ ፥ አጠመቀውም ። ከውኃውም ፡ ከወጡ ፡ በኋላ ፡ የጌታ ፡ መንፈስ ፡ ፊልጶስን ፡ ነጠቀው ፤ ጃንደረባውም ፡ ሁለተኛ ፡ አላየውም ፥ ደስ ፡ ፵ ብሎት ፡ መንገዱን ፡ ይሄድ ፡ ነበርና ። ፊልጶስ ፡ ግን ፡ በአዛጦን ፡ ተገኘ ፥ ወደ ፡ ቂሣርያም ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ እየዞረ ፡ በከተማዎች ፡ ሁሉ ፡ ወንጌልን ፡ ይሰብክ ፡ ነበር ።

፰ ፡ ፭ ፡ ምዕ. ፮ ፥ ፭ ። ፳፭ ፡ መዝ. ፻፯ ፥ ፴፯ ። ፳፫ ፡ ዘዳግ. ፳፱ ፥ ፲፰ ፡ ኢሳ. ፶፰ ፥ ፮ ። ፳፯ ፡ ምዕ. ፩ ፥ ፲፱ ። ፳፯ ፡ ፩ ነገሥ. ፰ ፥ ፵፩—፵፫ ። ፴፪ ፡ ቆሮ. ፩ ፡ ምዕ. ፲ ፥ ፲፬ ፡ ፲፩ ፥ ፳፯ ፡ ፲፫ ፥ ፪ ፡ ፲፯ ፥ ፫ ፡ ፯ ፡ ፳ ፥ ፳፪ ። ፴፪ ፡ ፴፫ ፡ ኢሳ. ፶፫ ፥ ፯ ። ፴፬ ፡ ሉቃ. ፳፬ ፥ ፳፯ ። ፴፯ ፡ ማር. ፲፮ ፥ ፲፮ ። ፵ ፡ ቍ. ፳፱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ሳውል ፡ ግን ፡ የጌታን ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ እንዲገድላቸው ፡ ገና ፡ እየዛተ ፡ ወደ ፡ ሊቀ ፡ ካህ ፪ ናት ፡ ሄደ ፥ በዚህ ፡ መንገድ ፡ ያሉትንም ፡ ሰዎች ፡ ወንዶችንም ፡ ሴቶችንም ፡ ቢያገኝ ፥ እያሰረ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ያመጣቸው ፡ ዘንድ ፡ በደማስቆ ፡ ላሉት ፡ ምኵራቦች ፡ ደብዳቤ ፡ ከእርሱ ፡ ፫ ለመነ ። ሲሄድም ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፡ ድንገት ፡ በእርሱ ፡ ዙሪያ ፡ ከሰማይ ፡ ብር ፬ ሃን ፡ አንጸበረቀ ፤ በምድርም ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ሳለ ፡— ሳውል ፡ ሳውል ፥ ስለ ፡ ምን ፡ ታሳድደኛ ፭ ለህ ? የሚለውን ፡ ድምፅ ፡ ሰማ ። ጌታ ፡ ሆይ ፥ ማን ፡ ነህ ? አለው ። እርሱም ፡— አንተ ፡ የም ታሳድደኝ ፡ እኔ ፡ ኢየሱስ ፡ ነኝ ፤ የመውጊያ ውን ፡ ብረት ፡ ብትቃወም ፡ ለአንተ ፡ ይብስብ ፮ ሃል ፡ አለው ። እየተንቀጠቀጠና ፡ እየተደነቀ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ምን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ ትወዳለህ ? አለው ። ጌታም ፡— ተነሥተህ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ግባና ፡ ታደርገው ፡ ዘንድ ፡ የሚያስፈልግህን ፡ ፯ ይነግሩሃል ፡ አለው ። ከእርሱም ፡ ጋር ፡ በመን ገድ ፡ የሄዱ ፡ ሰዎች ፡ ድምፁን ፡ እየሰሙ ፡ ማንን ፡ ፰ ግን ፡ ሳያዩ ፡ እንደ ፡ ዲዳዎች ፡ ቆሙ ። ሳውልም ፡ ከምድር ፡ ተነሣ ፥ ዓይኖቹም ፡ በተከፈቱ ፡ ጊዜ ፡ ምንም ፡ አላየም ፤ እጁንም ፡ ይዘው ፡ እየመሩ ፡ ፱ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ አገቡት ። ሳያይም ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ኖረ ፤ አልበላምም ፡ አልጠጣምም ።

፲ በደማስቆም ፡ ሐናንያ ፡ የሚሉት ፡ አንድ ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ነበረ ፤ ጌታም ፡ በራእይ ፡— ሐናንያ ፡ ሆይ ፥ አለው ። እርሱም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ እነ ፲፩ ሆኝ ፡ አለ ። ጌታም ፡— ተነሥተህ ፡ ቅን ፡ ወደ ሚባለው ፡ መንገድ ፡ ሂድ ፥ በይሁዳ ፡ ቤትም ፡ ሳውል ፡ የሚሉትን ፡ አንድ ፡ የጠርሴስ ፡ ሰው ፡ ፲፪ ፈልግ ፤ እነሆ ፥ እርሱ ፡ ይጸልያልና ፤ ሐናንያ ፡ የሚሉትም ፡ ሰው ፡ ገብቶ ፡ ደግሞ ፡ እንዲያይ ፡ ፲፫ እጁን ፡ ሲጭንበት ፡ አይቶአል ፡ አለው ። ሐና ንያም ፡ መለሰ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ በኢየሩሳሌም ፡ በቅዱሳንህ ፡ ላይ ፡ ስንት ፡ ክፉ ፡ እንዳደረገ ፡ ስለ ፲፬ ዚህ ፡ ሰው ፡ ከብዙዎች ፡ ሰምቼአለሁ ፤ በዚህም ፡ ስምህን ፡ የሚጠሩትን ፡ ሁሉ ፡ ለማሰር ፡ ከካ ህናት ፡ አለቆች ፡ ሥልጣን ፡ አለው ፡ አለ ። ፲፭ ጌታም ፡— ይህ ፡ በአሕዛብም ፡ በነገሥታትም ፡ በእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ስሜን ፡ ይሸከም ፡ ዘንድ ፡ ለእኔ ፡ የተመረጠ ፡ ዕቃ ፡ ነውና ፡ ሂድ ፤ ፲፮ ስለ ፡ ስሜ ፡ ስንት ፡ መከራ ፡ ሊቀበል ፡ እንዲያ ስፈልገው ፡ እኔ ፡ አመለክተዋለሁና ፡ አለው ። ፲፯ ሐናንያም ፡ ሄዶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ገባ ፥ እጁንም ፡ ጭኖበት ፡— ወንድሜ ፡ ሳውል ፡ ሆይ ፥ ጌታ ፥ እርሱም ፡ በመጣህበት ፡ መንገድ ፡ የታየህ ፡ ኢየ ሱስ ፡ ነው ፥ ደግሞ ፡ ታይ ፡ ዘንድና ፡ መንፈስ ፡ ፲፰ ቅዱስ ፡ ይሞላብህ ፡ ዘንድ ፡ ላከኝ ፡ አለ ። ወዲ ያውም ፡ እንደ ፡ ቅርፊት ፡ ያለ ፡ ከዓይኑ ፡ ወደቀ ፥ ያን ፡ ጊዜም ፡ ደግሞ ፡ አየ ፤ ተነሥቶም ፡ ተጠ ፲፱ መቀ ፥ መብልም ፡ በልቶ ፡ በረታ ።

በደማስቆም ፡ ካሉት ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ጋር ፡ ፳ ጥቂት ፡ ቀን ፡ ኖረ ። ወዲያውም ፡ ስለ ፡ ኢየ ሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እርሱ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ፳፩ እንደ ፡ ሆነ ፡ በምኵራቦች ፡ ሰበከ ። የሰሙትም ፡ ሁሉ ፡ ተገረሙና ፡— ይህ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ይህን ፡ ስም ፡ የሚጠሩትን ፡ ያጠፋ ፡ አይደለምን ? ስለ ዚህስ ፡ ታስረው ፡ ወደ ፡ ከህናት ፡ አለቆች ፡ ይወ ስዳቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደዚህ ፡ አልመጣምን ? አሉ ። ፳፪ ሳውል ፡ ግን ፡ እየበረታ ፡ ሄደ ፥ በደማስቆም ፡ ለተቀመጡት ፡ አይሁድ ፡ ይህ ፡ ክርስቶስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስረድቶ ፡ መልስ ፡ ያሳጣቸው ፡ ነበር ።

፳፫ ብዙ ፡ ቀንም ፡ ሲሞላ ፡ አይሁድ ፡ ሊገድሉት ፡ ፳፬ ተማከሩ ፤ ሳውል ፡ ግን ፡ አሳባቸውን ፡ አወቀ ። ይገድሉትም ፡ ዘንድ ፡ በሌሊትና ፡ በቀን ፡ የከተ ፳፭ ማይቱን ፡ በር ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቁ ፡ ነበር ፤ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ግን ፡ በሌሊት ፡ ወስደው ፡ በቅጥር ፡ ላይ ፡ አሳልፈው ፡ በቅርጫት ፡ አወረዱት ።

፳፮ ሳውልም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ጋር ፡ ይተባበር ፡ ዘንድ ፡ ሞከረ ፤ ሁሉም ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፳፯ ስላላመኑ ፡ ፈሩት ። በርናባስ ፡ ግን ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ ሐዋርያት ፡ አገባውና ፡ ጌታን ፡ በመንገድ ፡ እንዴት ፡ እንዳየውና ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ በደማ ስቆም ፡ በኢየሱስ ፡ ስም ፡ ደፍሮ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ፳፰ ነገረ ፡ ተረከላቸው ። በጌታም ፡ በኢየሱስ ፡ ስም ፡ ደፍሮ ፡ እየተናገረ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ሲወጣና ፡ ፳፱ ሲገባ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፤ ከግሪክ ፡ አገርም ፡ መጥተው ፡ ከነበሩት ፡ አይሁድ ፡ ጋር ፡ ይነጋገ ርና ፡ ይከራከር ፡ ነበር ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ ሊገድ ፴ ሉት ፡ ፈለጉ ። ወንድሞችም ፡ ይህን ፡ በወቁ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ቂሣርያ ፡ ወሰዱት ፡ ወደ ፡ ጠርሴ ስም ፡ ሰደዱት ።

፴፩ በይሁዳም ፡ ሁሉና ፡ በገሊላ ፡ በሰማርያም ፡ የነበሩት ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ ለሰላም ፡ ኖሩ ፡ ታነጹም ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፍርሃ ትና ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ መጽናናት ፡ እየሄዱ ፡ ይበዙ ፡ ነበር ።

፴፪ ጴጥሮስም ፡ በየስፍራው ፡ ሁሉ ፡ ሲዞር ፡ በልዳ ፡ ፴፫ ወደሚኖሩ ፡ ቅዱሳን ፡ ደግሞ ፡ ወረደ ። በዚያም ፡ ከስምንት ፡ ዓመት ፡ ጀምሮ ፡ በአልጋ ፡ ላይ ፡ ተኝቶ ፡ የነበረውን ፡ ኤንያ ፡ የሚሉትን ፡ አንድ ፡ ፴፬ ሰው ፡ አገኘ ፤ እርሱም ፡ ሽባ ፡ ነበረ ። ጴጥሮ ስም ፡— ኤንያ ፡ ሆይ ፥ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ይፈ ውስሃል ፤ ተነሣ ፡ ለራስህም ፡ አንጥፍ ፡ አለው ። ፴፭ ወዲያውም ፡ ተነሣ ። በልዳና ፡ በሰሮናም ፡ የሚ ኖሩ ፡ ሁሉ ፡ እርሱን ፡ አይተው ፡ ወደ ፡ ጌታ ፡ ዞሩ ፡ አሉ ።

፴፮ በኢዮጴም ፡ ጣቢታ ፡ የሚሉአት ፡ አንዲት ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ነበረች ፥ ትርጓሜውም ፡ ዶርቃ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ እርስዋም ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ የም ፴፯ ታደርገው ፡ ምጽዋትም ፡ የምታደርግ ፡ ነበረች ። በዚ

፱። ፩–፲፱፤ ም. ፳፪፥፮–፲፮፤ ፳፮፥፱–፲፰። ፭፤ ም. ፳፮፥፲፬። ፲፮፤ ፪ ቆሮ. ፲፩፥ ፳፫–፳፯። ፲፱፤ ገላ. ፩፥፲፯–፲፰። ፳፫፤ ገላ. ፩፥፲፰። ፳፫፤ ፳፭፤ ፪ ቆሮ. ፲፩፥፴፪፡፴፫። ፳፯፤ ም. ፬፥፴፮።

ያም፡ወራት፡ታመመችና፡ሞተች፤ አጥበ ፴፰ ውም፡በሰገነት፡አኖሩአት ። ልዳም፡ለኢዮጴ፡ ቅርብ፡ናትና፡ደቀ፡መዛሙርት፡ጴጥሮስ፡ በዚያ፡እንዳለ፡ሰምተው÷ወደ፡እነርሱ፡ከመ ምጣት፡እንዳይዘገይ፡እየለመኑ፡ሁለት፡ሰዎች፡ ፴፱ ወደ፡እርሱ፡ላኩ ። ጴጥሮስም፡ተነሥቶ፡ከእ ነርሱ፡ጋር፡መጣ፤ በደረሰም፡ጊዜ፡በሰገነት፡ አወጡት፤ መበለቶችም፡ሁሉ፡እያለቀሱ፡ ዶርቃ፡ከእነርሱ፡ጋር፡ሳለች፡ያደረገቻቸ ውን፡ቀሚሶችንና፡ልብሶችን፡ሁሉ፡እያሳዩት፡ ፵ በፊቱ፡ቆሙ ። ጴጥሮስም፡ሁሉን፡ወደ፡ውጭ፡ አስወጥቶ፡ተንበርክኮም፡ጸለየ÷ወደ፡ሬሳ ውም፡ዘወር፡ብሎ፦ ጣቢታ፡ሆይ÷ተነሺ፡ አላት ። እርስዋም፡ዓይኖችዋን፡ከፈተች፡ጴጥ ፵፩ ሮስንም፡ባየች፡ጊዜ፡ተቀመጠች ። እጁንም፡ ለእርስዋ፡ሰጥቶ፡አስነሣት፤ ቅዱሳንንና፡መበ ለቶችንም፡ጠራ፡ሕያውም፡ሆና፡በፊታቸው፡ ፵፪ አቆማት ። ይህም፡በኢዮጴ፡ሁሉ፡የታወቀ፡ ፵፫ ሆነ÷ብዙ፡ሰዎችም፡በጌታ፡አመኑ ። በኢዮ ጴም፡ስምዖን፡ከሚሉት፡ከአንድ፡ቍርበት፡ ፋቂ፡ጋር፡አያሌ፡ቀን፡ኖረ ።

## ምዕራፍ፡፲ ።

፩ በቂሣርያም፡ኢጣሊቄ፡ከሚሉት፡ጭፍራ፡ የመቶ፡አለቃ፡የሆነ፡ቆርኔሌዎስ፡የሚሉት፡ ፪ አንድ፡ሰው፡ነበረ ። እርሱም፡ከቤተ፡ሰዎቹ፡ ሁሉ፡ጋር፡እግዚአብሔርን፡የሚያመልክና፡ የሚፈራ፡ለሕዝብም፡እጅግ፡ምጽዋት፡የሚ ያደርግ፡ወደ፡እግዚአብሔርም፡ሁልጊዜ፡ ፫ የሚጸልይ፡ነበረ ። ከቀኑም፡ዘጠኝ፡ሰዓት፡ ያህል፦ ቆርኔሌዎስ፡ሆይ፡የሚለው፡የእግ ዚአብሔር፡መልአክ፡ወደ፡እርሱ፡ሲገባ፡በራ ፬ እይ፡በግልጥ፡አየው ። እርሱም፡ትኵር፡ ብሎ፡ሲመለከተው፡ደንግጦ፦ ጌታ፡ሆይ÷ ምንድር፡ነው? አለ ። መልአኩም፡አለው፦ ጸሎትህና፡ምጽዋትህ፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡ ፭ ለመታሰቢያ፡እንዲሆን፡ዐረገ ። አሁንም፡ ወደ፡ኢዮጴ፡ሰዎችን፡ልከህ፡ጴጥሮስ፡የሚ ፮ ባለውን፡ስምዖንን፡አስመጣ ። እርሱ፡ቤቱ፡ በባሕር፡አጠገብ፡ባለው፡በቍርበት፡ፋቂው፡ በስምዖን፡ዘንድ፡እንግድነት፡ተቀምጦአል፤ ልታደርገው፡የሚገባህን፡እርሱ፡ይነግርሃል ። ፯ የተናገረውም፡መልአክ፡በሄደ፡ጊዜ÷ከሎሌ ዎቹ፡ሁለቱን÷ከማይለዩትም፡ጭፍሮቹ፡እግ ዚአብሔርን፡የሚያመልክ፡አንዱን፡ወታደር፡ ፰ ጠርቶ÷ነገሩን፡ሁሉ፡ተረከላቸው፡ወደ፡ ኢዮጴም፡ላካቸው ።

፱ እነርሱም፡በነገው፡ሲሄዱ፡ወደ፡ከተማም፡ ሲቀርቡ÷ጴጥሮስ፡በስድስት፡ሰዓት፡ያህል፡ ፲ ይጸልይ፡ዘንድ፡ወደ፡ጣራው፡ወጣ ። ተር በም፡ሊበላ፡ወደደ፤ ሲያዘጋጁለት፡ሳሉም፡ ፲፩ ተመስጦ፡መጣበት፤ ሰማይም፡ተከፍቶ፡በአ ራት፡ማዕዘን፡የተያዘ፡ታላቅ፡ሸማ፡የሚመ ፲፪ ስል፡ዕቃ፡ወደ፡ምድር፡ሲወርድ፡አየ፤ በዚ ያውም፡አራት፡እግር፡ያላቸው፡ሁሉ፡አራ ዊትም፡በምድርም፡የሚንቀሳቀሱት፡የሰማይ፡ ፲፫ ወፎችም፡ነበሩበት ። ጴጥሮስ፡ሆይ÷ተነ ሣና፡አርደህ፡ብላ፡የሚልም፡ድምፅ፡ወደ፡ ፲፬ እርሱ፡መጣ ። ጴጥሮስ፡ግን፦ ጌታ፡ሆይ÷ አይሆንም፤ አንዳች፡ርኵስ፡የሚያስጸይፍም፡ ፲፭ ከቶ፡በልቼ፡አላውቅምና፡አለ ። ደግሞም፡ ሁለተኛ፦ እግዚአብሔር፡ያነጻውን፡አንተ፡ አታርክሰው፡የሚል፡ድምፅ፡ወደ፡እርሱ፡ ፲፮ መጣ ። ይህም፡ሦስት፡ጊዜ፡ሆነ÷ወዲያውም፡ ዕቃው፡ወደ፡ሰማይ፡ተወሰደ ።

፲፯ ጴጥሮስም፡ስላየው፡ራእይ፦ ምን፡ይሆን? ብሎ፡በልቡ፡ሲያመነታ÷እነሆ÷ቆርኔሌዎስ፡ የላካቸው፡ሰዎች፡ስለ፡ስምዖን፡ቤት፡ጠይ ፲፰ ቀው፡ወደ፡ደጁ፡ቀረቡ፤ ድምፃቸውንም፡ ከፍ፡አድርገው፦ ጴጥሮስ፡የተባለው፡ስም ዖን፡በዚህ፡እንግድነት፡ተቀምጦአልን? ብለው፡ ፲፱ ይጠይቁ፡ነበር ። ጴጥሮስም፡ስለ፡ራእዩ፡ሲያ ወጣ፡ሲያወርድ፡ሳለ÷መንፈስ፦ እነሆ÷ ፳ ሦስት፡ሰዎች፡ይፈልጉሃል፤ ተነሥተህ፡ ውረድ÷እኔም፡ልኬአቸዋለሁና፡ሳትጠራ ፳፩ ጠር፡ከእነርሱ፡ጋር፡ሂድ፡አለው ። ጴጥሮ ስም፡ወደ፡ሰዎቹ፡ወርዶ፦ እነሆ÷የምትፈ ልጉኝ፡እኔ፡ነኝ፤ የመጣችሁበትስ፡ምክን ፳፪ ያት፡ምንድር፡ነው? አላቸው ። እነርሱም፦ ጻድቅ፡ሰው፡እግዚአብሔርንም፡የሚፈራ፡ በአይሁድም፡ሕዝብ፡ሁሉ፡የተመሰከረለት፡ የመቶ፡አለቃ፡ቆርኔሌዎስ፡ወደ፡ቤቱ፡ያስመ ጣህ፡ዘንድ፡ከአንተም፡ቃል፡ይሰማ፡ዘንድ፡ ፳፫ ከቅዱስ፡መልአክ፡ተረዳ፡አሉት ። እርሱም፡ ወደ፡ውስጥ፡ጠርቶ፡እንግድነት፡ተቀበላ ቸው ።

በነገውም፡ተነሥቶ፡ከእነርሱ፡ጋር፡ወጣ÷ በኢዮጴም፡ከነበሩት፡ወንድሞች፡አንዳንዶቹ፡ ፳፬ ከእርሱ፡ጋር፡አብረው፡ሄዱ ። በነገውም፡ ወደ፡ቂሣርያ፡ገቡ፤ ቆርኔሌዎስም፡ዘመዶቹ ንና፡የቅርብ፡ወዳጆቹን፡በአንድነት፡ጠርቶ፡ ፳፭ ይጠባበቃቸው፡ነበር ። ጴጥሮስም፡በገባ፡ ጊዜ፡ቆርኔሌዎስ፡ተገናኝቶ፡ከእግሩ፡በታች፡ ፳፮ ወድቆና፡ሰገደለት ። ጴጥሮስ፡ግን፦ ተነሣ፤ እኔ፡ራሴ፡ደግሞ፡ሰው፡ነኝ፡ብሎ፡አስነሣው ። ፳፯ ከእርሱም፡ጋር፡እየተነጋገረ፡ገባ÷ብዙዎችም፡ ፳፰ ተከማችተው፡አግኝቶ፦ አይሁዳዊ፡ሰው፡ ከሌላ፡ወገን፡ጋር፡ይተባበር፡ወይም፡ይቃ ረብ፡ዘንድ፡እንዳልተፈቀደ፡እናንተ፡ታው ቃላችሁ፤ ለእኔ፡ግን፡እግዚአብሔር፡ማንንም፡ ሰው፡ርኵስና፡የሚያስጸይፍ፡ነው፡እንዳልል፡ አሳየኝ፤ ስለዚህም፡ደግሞ፡ብትጠሩኝ፡ስል

፱። ፴፮፤ ማቴ. ፱፡፳፭። ፴፱፤ ዮሐ. ፲፩፡፵፭።
፲። ፫፤ ም. ፳፡፲፱። ፮፤ ም. ፱፡፵፫። ፲፱፤ ዘሌዋ. ፲፩፡፪–፵፯። ፲፭፤ ማቴ. ፲፭፡፲፩። ፲፱፤ ም. ፰፡፳፱። ፳፰፤ ዮሐ. ፬፡፱፤ ፲፰፡፳፰።

ከራከር ፡ መጣሁ ። አሁንም ፡ በምን ፡ ምክን ያት ፡ አስመጣችሁኝ ? ብዬ ፡ እጠይቃችኋለሁ ፡ አላቸው ።

፴ ቆርኔሌዎስም ፡ እንዲህ ፡ አለው ፦ በዚች ፡ ሰዓት ፡ የዛሬ ፡ አራት ፡ ቀን ፡ የዘጠኝ ፡ ሰዓት ፡ ጸሎት ፡ በቤቴ ፡ እጸልይ ፡ ነበር ፤ እነሆም ፥ የሚያንጸባርቅ ፡ ልብስ ፡ የለበሰ ፡ ሰው ፡ በፊቴ ፡ ፴፩ ቆመና ፦ ቆርኔሌዎስ ፡ ሆይ ፥ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ጸሎትህ ፡ ተሰማ ፡ ምጽዋትህም ፡ ታሰበ ። ፴፪ እንግዲህ ፡ ወደ ፡ ኢዮጴ ፡ ልከህ ፡ ጴጥሮስ ፡ የተ ባለውን ፡ ስምዖንን ፡ አስጠራ ፤ እርሱ ፡ በቍርበት ፡ ፋቂው ፡ በስምዖን ፡ ቤት ፡ በባሕር ፡ አጠ ፴፫ ገብ ፡ እንግድነት ፡ ተቀምጦአል ፡ አለኝ ። ስለ ዚህ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ላክሁ ፥ አንተም ፡ በመምጣትህ ፡ መልካም ፡ አድርገሃል ። እንግ ዲህ ፡ እንተ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የታዘዝ ኸውን ፡ ሁሉ ፡ እንድንሰማ ፡ እኛ ፡ ሁላችን ፡ አሁን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በዚህ ፡ አለን ።

፴፬፡፴፭ ጴጥሮስም ፡ አፉን ፡ ከፍቶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ እግዚአብሔር ፡ ለሰው ፡ ፊት ፡ እንዳያደላ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ እርሱን ፡ የሚፈራና ፡ ጽድቅን ፡ የሚያደርግ ፡ በእርሱ ፡ የተወደደ ፡ ፴፮ እንደ ፡ ሆነ ፡ በእውነት ፡ አስተዋልሁ ። የሁሉ ፡ ጌታ ፡ በሚሆን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሰላምን ፡ እየሰበከ ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ልጆች ፡ ፴፯ ላከ ። ዮሐንስ ፡ ከሰበከው ፡ ጥምቀት ፡ በኋላ ፡ ከገሊላ ፡ ጀምሮ ፡ በይሁዳ ፡ ሁሉ ፡ የሆነውን ፡ ፴፰ ነገር ፡ እናንተ ፡ታውቃላችሁ ። እግዚአብሔር ፡ የናዝሬቱን ፡ ኢየሱስን ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በኃ ይልም ፡ቀባው ፥ እርሱም ፡ መልካም ፡ እያደረገ ፡ በዲያብሎስም ፡ የተገዙትን ፡ ሁሉ ፡ እየፈወሰ ፡ ዞረ ፥ እግዚአብሔር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረና ፤ ፴፱ እኛም ፡ በአይሁድ ፡ አገርና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በደረገው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ምስክሮች ፡ ነን ፤ እር ሱንም ፡ በእንጨት ፡ ላይ ፡ ሰቅለው ፡ገደሉት ። ፵ እርሱን ፡ እግዚአብሔር ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ፵፩ አስነሣው ፡ ይገለጥም ፡ ዘንድ ፡ ሰጠው ፤ ይኸ ውም ፡ ለሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ አይደለም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አስቀድሞ ፡ የተመረጡ ፡ ምስ ክሮች ፡ ለሆንን ፡ ለእኛ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ከሙታ ንም ፡ ከተነሣ ፡ በኋላ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የበላን ፡ ፵፪ የጠጣንም ፡ እኛ ፡ ነን ። ለሕዝብም ፡ እንድንሰ ብከና ፡ በሕያዋንና ፡ በሙታን ፡ ሊፈርድ ፡ በእ ግዚአብሔር ፡ የተወሰነ ፡ እርሱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፵፫ እንመሰክር ፡ ዘንድ ፡ አዘዘን ። በእርሱ ፡ የሚያ ምን ፡ ሁሉ ፡ በስሙ ፡ የኃጢአቱን ፡ ስርየት ፡ እንዲቀበል ፡ነቢያት ፡ ሁሉ ፡ ይመሰክሩለታል ።

፵፬ ጴጥሮስ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ገና ፡ ሲናገር ፡ ቃሉን ፡ በሰሙት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ወረደ ። ፵፭ ከጴጥሮስም ፡ ጋር ፡ የመጡት ፡ ሁሉ ፡ ከተገረ ዙት ፡ ወገን ፡ የሆኑ ፡ ምዕመናን ፡ በአሕዛብ ፡ ላይ ፡ ደግሞ ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ስጦታ ፡ ስለ ፡ ፈሰሰ ፡ ተገረሙ ፤ ፵፮ በልሳኖች ፡ ሲናገሩ ፡ እግዚ አብሔርንም ፡ ሲያከብሩ ፡ ሰምተዋቸዋልና ። ፵፯ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ጴጥሮስ ፡ መልሶ ፦ እነዚህ ፡ እንደ ፡ እኛ ፡ ደግሞ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ የተ ቀበሉ ፡ እንዳይጠመቁ ፡ውኃን ፡ ይከለክላቸው ፡ ዘንድ ፡ የሚችል ፡ ማን ፡ ነው ? አለ ። ፵፰ በኢየ ሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስምም ፡ ይጠመቁ ፡ ዘንድ ፡ አዘ ዛቸው ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጥቂት ፡ ቀን ፡ እንዲቀ መጥ ፡ ለመኑት ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ ሐዋርያትና ፡ በይሁዳም ፡ የነበሩት ፡ ወንድ ሞች ፡ አሕዛብ ፡ ደግሞ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ እንደ ፡ ተቀበሉ ፡ ሰሙ ። ፪ ጴጥሮስም ፡ ወደ ፡ ኢየ ሩሳሌም ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ከተገረዙት ፡ ወገን ፡ የሆ ኑት ፡ ሰዎች ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተከራከረው ፦ ፫ ወዳልተገረዙ ፡ ሰዎች ፡ ገብተህ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ፬ በላህ ፡ አሉት ። ጴጥሮስ ፡ ግን ፡ ከመጀመሪያው ፡ ጀምሮ ፡ በተራ ፡ ገለጠላቸው ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦ ፭ እኔ ፡ በኢዮጴ ፡ ከተማ ፡ ስጸልይ ፡ ሳለሁ ፡ ተመ ስጬ ፡ ራእይን ፡ አየሁ ፤ ታላቅ ፡ ሸማ ፡ የመሰለ ፡ ዕቃ ፡ በአራት ፡ ማዕዘን ፡ ተይዞ ፡ ከሰማይ ፡ ወረ ፮ ደና ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጣ ፤ ይህንም ፡ ትኵር ፡ ብዬ ፡ ስመለከት ፡ አራት ፡ እግር ፡ ያላቸውን ፡ የምድር ፡ እንስሶች ፡ አራዊትንም ፡ ተንቀሳቃሾችንም ፡ ፯ የሰማይ ፡ ወፎችንም ፡ አየሁ ። ጴጥሮስ ፡ ሆይ ፥ ተነሣና ፡ አርደህ ፡ ብላ ፡ የሚለኝንም ፡ ድምፅ ፡ ፰ ሰማሁ ። እኔም ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ አይሆንም ፤ ርኵስ ፡ ወይም ፡ የሚያስጸይፍ ፡ ከቶ ፡ ወደ ፡ ፱ አፌ ፡ ገብቶ ፡ አያውቅምና ፡ አልሁ ። ሁለተ ኛም ፦ እግዚአብሔር ፡ ያነጻውን ፡ አንተ ፡ አታ ርክሰው ፡ የሚል ፡ ድምፅ ፡ ከሰማይ ፡ መለሰልኝ ። ፲ ይህም ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ሆነ ፡ እንደ ፡ ገናም ፡ ሁሉ ፡ ፲፩ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ተሳበ ። እነሆም ፥ ያን ፡ ጊዜ ፡ ሦስት ፡ ሰዎች ፡ ከቂሣርያ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ተልከው ፡ ፲፪ ወዳለሁበት ፡ ቤት ፡ ቀረቡ ። መንፈስም ፡ ሳል ጠራጠር ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ እሄድ ፡ ዘንድ ፡ ነገ ረኝ ። እነዚህም ፡ስድስቱ ፡ ወንድሞች ፡ደግሞ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ መጡ ፡ ወደዚያ ፡ ሰውም ፡ ቤት ፡ ፲፫ ገባን ። እርሱም ፡ መልአክ ፡ በቤቱ ፡ ቆሞ ፡ እንዳ የና ፦ ወደ ፡ ኢዮጴ ፡ ሰዎች ፡ ልከህ ፡ ጴጥሮስ ፡ ፲፬ የተባለውን ፡ ስምዖንን ፡ አስመጣ ፤ እርሱም ፡ አንተና ፡ የቤትህ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ የምትድኑበ ትን ፡ ነገር ፡ ይነግርሃል ፡ እንዳለው ፡ ነገረን ። ፲፭ ለመናገርም ፡ በጀመርሁ ፡ ጊዜ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ለእኛ ፡ ደግሞ ፡ በመጀመሪያ ፡ እንደ ፡ ወረደ ፡ ፲፮ ለእነርሱ ፡ ወረደላቸው ። ዮሐንስ ፡ በውኃ ፡ አጠ መቀ ፡ እናንተ ፡ ግን ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ትጠ መቃላችሁ ፡ ያለውም ፡ የጌታ ፡ ቃል ፡ ትዝ ፡ ፲፯ አለኝ ። እንግዲህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በጌታ ፡ በኢ

፲ ። ፴፬ ፤ ዘዳግ. ፲ ፥ ፲፯ ። ፴፮ ፤ ሮሜ. ፲ ፥ ፲፪ ። ፴፯ ፤ መዝ. ፻፯ ፥ ፳ ። ፴፰ ፤ ኢሳ. ፷፩ ፥ ፩ ። ፵፩—፵፪ ፤ ሉቃ. ፳፬ ፥ ፵፰—፵፰ ፤ ዮሐ. ፳ ፥ ፳፱ ። ፵፯ ፤ ም. ፪ ፥ ፬ ።

፲፩ ። ፩ ፤ ገላ. ፪ ፥ ፲፪ ። ፭—፲፯ ፤ ም. ፲ ፥ ፱—፵፰ ። ፲፮ ፤ ም. ፩ ፥ ፭ ።

የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ላመነው ፡ ለእኛ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ሰጠን ፡ ያን ፡ ስጦታ ፡ ለእነርሱ ፡ ከሰጠ ፥ እግዚአብሔርን ፡ ለመከልከል ፡ አችል ፡ ዘንድ ፡ እኔ ፡ ማን ፡ ነበርሁ ? ፲፰ ይህን ፡ በሰሙ ፡ ጊዜም ፡ ዝም ፡ አሉና ፡— እንኪያስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአሕዛብ ፡ ደግሞ ፡ ለሕይወት ፡ የሚሆን ፡ ንስሐን ፡ ሰጣቸው ፡ እያሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አከበሩ ።

፲፱ በእስጢፋኖስም ፡ ላይ ፡ በተደረገው ፡ መከራ ፡ የተበተኑት ፡ እስከ ፡ ፊንቄ ፡ እስከ ፡ ቆጵሮስም ፡ እስከ ፡ አንጾኪያም ፡ ድረስ ፡ ዞሩ ፥ ቃሉንም ፡ ለአይሁድ ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ ለአንድ ፡ ስንኳ ፡ አይ ናገሩም ፡ ነበር ። ፳ ከእነርሱ ፡ ግን ፡ የቆጵሮስና ፡ የቀሬና ፡ ሰዎች ፡ የነበሩት ፡ አንዳንዶቹ ፡ ወደ ፡ አንጾኪያ ፡ መጥተው ፡ የጌታን ፡ የኢየሱስን ፡ ወንጌል ፡ እየሰበኩ ፡ ለግሪክ ፡ ሰዎች ፡ ተናገሩ ። ፳፩ የጌታም ፡ እጅ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ነበረ ፤ ቍጥ ራቸውም ፡ እጅግ ፡ የሚሆን ፡ ሰዎች ፡ አምነው ፡ ወደ ፡ ጌታ ፡ ዞወር ፡ አሉ ። ፳፪ ወሬውም ፡ በኢየሩ ሳሌም ፡ ባለችው ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ስለ ፡ እነ ርሱ ፡ ተሰማ ፥ በርናባስንም ፡ ወደ ፡ አንጾኪያ ፡ ላኩት ፤ ፳፫ እርሱም ፡ መጥቶ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ጸጋ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ አለው ፥ ሁሉንም ፡ በልባ ቸው ፡ ፈቃድ ፡ በጌታ ፡ ጸንተው ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡ መከራቸው ፤ ፳፬ ደግ ፡ ሰውና ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ እምነትም ፡ የሞላበት ፡ ነበረና ። ብዙ ፡ ሕዝብም ፡ ወደ ፡ ጌታ ፡ ተጨመሩ ። ፳፭ በርናባስም ፡ ሳውልን ፡ ሊፈልግ ፡ ወደ ፡ ጠርሴስ ፡ ወጣ ፤ ፳፮ በገኘውም ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ አንጾኪያ ፡ አመጣው ። በቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ሙሉ ፡ ተሰበ ሰቡ ፥ ብዙ ፡ ሕዝብንም ፡ አስተማሩ ፤ ደቀ ፡ መዛ ሙርትም ፡ መጀመሪያ ፡ በአንጾኪያ ፡ ክርስቲ ያን ፡ ተባሉ ።

፳፯ በዚያም ፡ ወራት ፡ ነቢያት ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ አንጾኪያ ፡ ወረዱ ፤ ፳፰ ከእነርሱም ፡ አጋቦስ ፡ የሚሉት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ተነሥቶ ፡ በዓለም ፡ ሁሉ ፡ ታላቅ ፡ ራብ ፡ ሊሆን ፡ እንዳለው ፡ በመን ፈስ ፡ አመለከተ ፤ ይህም ፡ በቀላውዴዎስ ፡ ቄሣር ፡ ዘመን ፡ ሆነ ። ፳፱ ደቀ ፡ መዛሙርትም ፡ እያንዳንዳ ቸው ፡ እንደ ፡ ችሎታቸው ፡ መጠን ፡ አዋጥተው ፡ በይሁዳ ፡ ለሚኖሩት ፡ ወንድሞች ፡ እርዳታን ፡ ይልኩ ፡ ዘንድ ፡ ወሰኑ ፤ ፴ እንዲህም ፡ ደግሞ ፡ አደረጉ ፥ በበርናባስና ፡ በሳውልም ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ ሽማግሌዎቹ ፡ ሰደዱት ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ንጉሡ ፡ ሄሮድስ ፡ መከራ ፡ ያጸናባቸው ፡ ዘንድ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በአ ንዳንዶቹ ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ ጫነባቸው ። ፪ የዮሐን ስንም ፡ ወንድም ፡ ያዕቆብን ፡ በሰይፍ ፡ ገደለው ። ፫ አይሁድንም ፡ ደስ ፡ እንዳሰኛቸው ፡ አይቶ ፡ ጨምሮ ፡ ጴጥሮስን ፡ ደግሞ ፡ ያዘው ። የቂጣ ፡ በዓልም ፡ ወራት ፡ ነበረ ። ፬ በያዘውም ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ወኅኒ ፡ አገባው ፤ ከፋሲካም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሕዝብ ፡ ያወጣው ፡ ዘንድ ፡ አስቦ ፡ እያንዳንዱ ፡ አራት ፡ ወታደሮች ፡ ሆነው ፡ እንዲጠብቁት ፡ ለአራት ፡ ጭፍራ ፡ ክፍል ፡ አሳልፎ ፡ ሰጠው ። ፭ ጴጥሮስም ፡ በወኅኒ ፡ ይጠበቅ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸሎት ፡ አጥብቆ ፡ ይደረግ ፡ ነበር ።

፮ ሄሮድስም ፡ ሊያወጣው ፡ ባሰበ ፡ ጊዜ ፥ በዚ ያች ፡ ሌሊት ፡ ጴጥሮስ ፡ በሁለት ፡ ሰንሰለት ፡ ታስሮ ፡ ከሁለት ፡ ወታደሮች ፡ መካከል ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ፤ ጠባቂዎችም ፡ በደጁ ፡ ፊት ፡ ሆነው ፡ ወኅኒውን ፡ ይጠብቁ ፡ ነበር ። ፯ እነሆም ፥ የጌታ ፡ መልአክ ፡ ቀረበ ፡ በቤትም ፡ ውስጥ ፡ ብርሃን ፡ በራ ፤ ጴጥሮስንም ፡ ጎድኑን ፡ መትቶ ፡ አነቃ ውና ፡— ፈጥንህ ፡ ተነሣ ፡ አለው ። ሰንሰለቶቹም ፡ ከእጁ ፡ ወደቁ ። ፰ መልአኩም ፡— ታጠቅና ፡ ጫማህን ፡ አግባ ፡ አለው ፥ እንዲሁም ፡ አደረገ ። ፱ ልብስህንም ፡ ልበስና ፡ ተከተለኝ ፡ አለው ። ወጥ ቶም ፡ ተከተለው ፤ ራእይንም ፡ የሚያይ ፡ ይመ ስለው ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በመልአኩ ፡ የሚደረገው ፡ ነገር ፡ እውነት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አላወቀም ። ፲ የመ ጀመሪያውንና ፡ የሁለተኛውንም ፡ ዘብ ፡ አል ፈው ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ወደሚያወጣው ፡ ወደ ፡ ብረቱ ፡ መዝጊያ ፡ ደረሱ ፤ እርሱም ፡ አውቆ ፡ ተከፈተላቸው ፤ ወጥተውም ፡ አንዲት ፡ ስላች ፡ አለፉ ፡ ወዲያውም ፡ መልአኩ ፡ ከእርሱ ፡ ተለየ ። ፲፩ ጴጥሮስም ፡ ወደ ፡ ልቡ ፡ ተመልሶ ፡— ጌታ ፡ መል አኩን ፡ ልኮ ፡ ከሄሮድስ ፡ እጅና ፡ የአይሁድ ፡ ሕዝብ ፡ ይጠብቁት ፡ ከነበረው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ አዳነኝ ፡ አሁን ፡ በእውነት ፡ አወቅሁ ፡ አለ ።

፲፪ ባስተዋለም ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ሰዎች ፡ ተከማ ችተው ፡ ይጸልዩበት ፡ ወደ ፡ ነበረው ፡ ማርቆስ ፡ ወደ ፡ ተባለው ፡ ወደ ፡ ዮሐንስ ፡ እናት ፡ ወደ ፡ ማርያም ፡ ቤት ፡ መጣ ። ፲፫ ጴጥሮስም ፡ የደጁን ፡ መዝጊያ ፡ ባንኳኳ ፡ ጊዜ ፡ ሮዴ ፡ የሚሉአት ፡ አንዲት ፡ ገረድ ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡ ቀረበች ፤ ፲፬ የጴ ጥሮስ ፡ ድምፅ ፡ መሆኑንም ፡ ባወቀች ፡ ጊዜ ፡ ከደስታዋ ፡ የተነሣ ፡ ደጁን ፡ አልከፈተችም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ውስጥ ፡ ሮጣ ፡ ጴጥሮስ ፡ በደጅ ፡ ፊት ፡ ቆሞ ፡ እንዳለ ፡ አወራች ። ፲፭ እነርሱም ፡— አብደሻል ፡ አሉአት ። እርስዋ ፡ ግን ፡ እንዲሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ታስረግጥ ፡ ነበር ። እነርሱም ፡— መልአኩ ፡ ነው ፡ አሉ ። ፲፮ ጴጥሮስ ፡ ግን ፡ ማንኳ ኳቱን ፡ አዘወተረ ፤ ከፍተውም ፡ አዩትና ፡ ተገ ረሙ ። ፲፯ ግን ፡ ዝም ፡ እንዲሉ ፡ በእጁ ፡ ጠቅሶ ፡ ጌታ ፡ ከወኅኒ ፡ እንዴት ፡ እንዳወጣው ፡ ተረከላ ቸውና ፡— ይህን ፡ ለያዕቆብና ፡ ለወንድሞች ፡ ንገሩ ፡ አላቸው ። ወጥቶም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ስፍራ ፡ ሄደ ።

፲፩ ። ፲፱ ፡ ምዕ. ፰ ፥ ፩—፬ ። ፳፬ ፡ ምዕ. ፮ ፥ ፭ ። ፳፰ ፡ ምዕ. ፲ ፥ ፵፫ ። ፳፱ ፡ ምዕ. ፳ ፥ ፳፱ ።
፲፪ ። ፪ ፡ ማቴ. ፬ ፥ ፳፩ ። ፫ ፡ ዘፀአ. ፲፪ ፥ ፲፭ ፡ ፲፭ ። ፯ ፡ ምዕ. ፭ ፥ ፲፱ ። ፲፪ ፡ ቈላ. ፬ ፥ ፲ ። ፲፭ ፡ ማቴ. ፲፰ ፥ ፲ ። ፲፯ ፡ ማቴ. ፲፫ ፥ ፶፭ ፡ ፩ ቆሮ. ፲፭ ፥ ፯ ፡ ገላ. ፩ ፥ ፲፱ ።

፲፰ በነጋም ፡ ጊዜ ፡— ጴጥሮስን ፡ ምን ፡ አግኝቶት ፡ ይሆን ? ብለው ፡ በጭፍሮች ፡ ዘንድ ፡ ብዙ ፡ ፲፱ ሁከት ፡ ሆነ ። ሄሮድስም ፡ አስፈልጎ ፡ ባጣው ፡ ጊዜ ፡ ጠባቂዎችን ፡ መረመረ ፡ ይገድሉአቸውም ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ ከይሁዳም ፡ ወደ ፡ ቂሣርያ ፡ ወርዶ ፡ በዚያ ፡ ተቀመጠ ።

፳ ከጢሮስና ፡ ከሲዶና ፡ ሰዎችም ፡ ጋር ፡ ተጣልቶ ፡ ነበር ፤ በአንድ ፡ ልብ ፡ ሆነውም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጡ ፥ የንጉሥንም ፡ ቢትወደድ ፡ ብላስጦስን ፡ እሺ ፡ አሰኝተው ፡ ዕርቅ ፡ ለመኑ ፥ አገራቸው ፡ ከንጉሥ ፡ አገር ፡ ምግብ ፡ ያገኝ ፡ ነበ ፳፩ ርና ። በተቀጠረ ፡ ቀንም ፡ ሄሮድስ ፡ ልብሰ ፡ መንግሥቱን ፡ ለብሶ ፡ በዙፋን ፡ ተቀመጠ ፡ እነርሱ ፳፪ ንም ፡ ተናገራቸው ፤ ሕዝቡም ፡— የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ ነው ፡ የሰውም ፡ አይደለም ፡ ፳፫ ብለው ፡ ጮኹ ። ለእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ ስላልሰጠ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ የጌታ ፡ መልአክ ፡ መታው ፡ በትልም ፡ ተበልቶ ፡ሞተ ።

፳፬ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ግን ፡ ያድግና ፡ ይበዛ ፡ ነበር ።

፳፭ በርናባስና ፡ ሳውልም ፡ አገልግሎታቸውን ፡ ፈጽመው ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ፥ ማርቆስ ፡ የተባለውን ፡ ዮሐንስንም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ይዘውት ፡ መጡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ በአንጾኪያም ፡ ባለችው ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ነቢያትና ፡ መምህራን ፡ ነበሩ ፤ እነርሱም ፡ በርናባስ ፥ ኔጌር ፡ የተባለው ፡ ስምዖንም ፥ የቀሬናው ፡ ሉክዮስም ፥ የአራተኛው ፡ ክፍል ፡ ገዥ ፡ የሄሮድስም ፡ ባለምዋል ፡ ምናሔ ፥ ሳውልም ፡ ነበሩ ። ፪ እነዚህም ፡ ጌታን ፡ ሲያመልኩና ፡ ሲጦሙ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡— በርናባስንና ፡ ሳውልን ፡ ለጠ ፫ ራኋቸው ፡ ሥራ ፡ ለዩልኝ ፡ አለ ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ከጦሙ ፡ ከጸለዩም ፡ እጃቸውንም ፡ ከጫኑ ፡ በኋላ ፡ አሰናበቱአቸው ።

፬ እነርሱም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ተልከው ፡ ወደ ፡ ሴሌውቅያ ፡ ወረዱ ፤ ከዚያም ፡ በመር ፭ ከብ ፡ ወደ ፡ ቆጵሮስ ፡ ሄዱ ። በሰላሚናም ፡ በነበሩ ፡ ጊዜ ፡ በአይሁድ ፡ ምኵራቦች ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ሰበኩ ፤ አገልጋይም ፡ ዮሐንስ ፡ ፮ ነበራቸው ። ደሴቲቱንም ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ጳፉ ፡ በዞሩ ፡ ጊዜ ፥ በርያሱስ ፡ የሚሉትን ፡ ጠንቋይና ፡ ሐሰተኛ ፡ ነቢይ ፡ የሆነውን ፡ አንድ ፡ አይሁዳዊ ፡ ፯ ሰው ፡ አገኙ ፤ እርሱም ፡ አስተዋይ ፡ ሰው ፡ ከሆነው ፡ ሰርግዮስ ፡ ጳውሎስ ፡ ከሚባለው ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ጋር ፡ ነበረ ። ይህም ፡ በርናባስንና ፡ ሳውልን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ጠርቶ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፰ ቃል ፡ ሊሰማ ፡ ፈለገ ። ጠንቋዩ ፡ ግን ፡ ኤልማስ ፥ ስሙ ፡ እንዲሁ ፡ ይተረጐማልና ፥ አገረ ፡ ገዡን ፡ ከማመን ፡ ሊያጣምም ፡ ፈልጎ ፡ ተቃወ ፱ ማቸው ። ጳውሎስ ፡ የተባለው ፡ ሳውል ፡ ግን ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ተሞልቶ ፡ ትኵር ፡ ብሎ ፡ ፲ ሲመለከተው ፡— አንተ ፡ ተንኰል ፡ ሁሉ ፡ ክፋትም ፡ ሁሉ ፡ የሞላብህ ፥ የዲያብሎስ ፡ ልጅ ፥ የጽድቅም ፡ ሁሉ ፡ ጠላት ፥ የቀናውን ፡ የጌታን ፡ ፲፩ መንገድ ፡ ከማጣመም ፡ አታርፍምን ? አሁንም ፥ እነሆ ፥ የጌታ ፡ እጅ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ናት ፥ ዕውርም ፡ ትሆናለህ ፡ እስከ ፡ ጊዜውም ፡ ፀሐይን ፡ አታይም ፡ አለው ። ያን ፡ ጊዜም ፡ ጭጋግና ፡ ጨለማ ፡ ወደቀበት ፥ በእጁም ፡ የሚመራውን ፡ ፲፪ እየዞረ ፡ ፈለገ ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አገረ ፡ ገዡ ፡ የተደረገውን ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ከጌታ ፡ ትምህርት ፡ የተነሣ ፡ ተገርሞ ፡ አመነ ።

፲፫ ጳውሎስም ፡ ከጓደኞቹ ፡ ጋር ፡ ከጳፉ ፡ ተነሥቶ ፡ የጵንፍልያ ፡ ወደምትሆን ፡ ወደ ፡ ጴርጌን ፡ መጣ ፤ ዮሐንስም ፡ ከእነርሱ ፡ ተለይቶ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳ ፲፬ ሌም ፡ ተመለሰ ። እነርሱ ፡ ግን ፡ ከጴርጌን ፡ አልፈው ፡ የጲስድያ ፡ ወደምትሆን ፡ ወደ ፡ አንጾኪያ ፡ ደረሱ ፤ በሰንበትም ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ምኵ ፲፭ ራብ ፡ ገብተው ፡ ተቀመጡ ። ሕግና ፡ ነቢያትም ፡ ከተነበቡ ፡ በኋላ ፡ የምኵራቡ ፡ አለቆች ፡— ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ሕዝብን ፡ የሚመክር ፡ ቃል ፡ እንዳላችሁ ፡ ተናገሩ ፡ ብለው ፡ ላኩባቸው ። ፲፮ ጳውሎስም ፡ ተነሣና ፡ በእጁ ፡ ጠቅሶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—

የእስራኤል ፡ ሰዎችና ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩት ፡ ሆይ ፥ ስሙ ። ፲፯ የዚህ ፡ የእስራኤል ፡ ሕዝብ ፡ አምላክ ፡ አባቶቻችንን ፡ መረጠ ፡ በግብፅ ፡ አገር ፡ በእንግድነት ፡ ሳሉ ፡ ሕዝቡን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጋቸው ፥ ከፍ ፡ ባለችውም ፡ ክንዱ ፡ ከዚያ ፡ ፲፰ አወጣቸው ። በበረሀም ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ ፲፱ መገባቸው ። በከነዓንም ፡ አገር ፡ ሰባት ፡ አሕዛብን ፡ አጥፍቶ ፡ ምድራቸውን ፡ አወረሳቸው ። ፳ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ እስከ ፡ ነቢዩ ፡ እስከ ፡ ሳሙኤል ፡ ድረስ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ ፳፩ መሳፍንትን ፡ ሰጣቸው ። ከዚያም ፡ወዲያ ፡ ንጉሥን ፡ ያነግሥላቸው ፡ ዘንድ ፡ ለመኑ ፥ እግዚአብሔርም ፡ ከብንያም ፡ ወገን ፡ የሚሆን ፡ ሰው ፡ የቂስን ፡ ልጅ ፡ ሳኦልን ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ሰጣቸው ፤ ፳፪ እርሱንም ፡ ከሻረው ፡ በኋላ ፡ ዳዊትን ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ እንዲነግሥ ፡ አስነሣው ፥ ሲመሰክርለትም ፡— እንደ ፡ ልቤ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ፈቃዴንም ፡ ሁሉ ፡ የሚያደርግ ፡ የእሴይን ፡ ልጅ ፡ ዳዊትን ፡ ፳፫ አገኘሁ ፡ አለ ። ከዚህም ፡ ሰው ፡ ዘር ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተስፋው ፡ ቃል ፡ ለእስራኤል ፡ መድኃኒትን ፡ እርሱም ፡ ኢየሱስን ፡ አመጣ ። ፳፬ ከመምጣቱ ፡ በፊት ፡ ዮሐንስ ፡ አስቀድሞ ፡ ለእስ

፲፪ ። ፳ ፤ ፩ ነገሥ. ፭ ፥ ፱ ፤ ፲፩ ፤ ሕዝ. ፳፯ ፥ ፲፯ ። ፳፫ ፤ ምሳ. ፳ ፥ ፲፱ ። ፳፭ ፤ ምዕ. ፲፭ ፥ ፴፱ ፤ ፵ ።

፲፫ ። ፪ ፤ ምዕ. ፳ ፥ ፳፬ ። ፫ ፤ ምዕ. ፮ ፥ ፮ ። ፭ ፤ ምዕ. ፲፱ ፥ ፲፱ ፤ ፳፭ ። ፲ ፤ ሆሴ. ፲፬ ፥ ፱ ፤ ዮሐ. ፰ ፥ ፵፬ ። ፲፭ ፤ ሉቃ. ፬ ፥ ፲፯ ። ፲፯ ፤ ዘፀአ. ፮ ፥ ፮ ፤ ፯ ። ፲፰ ፤ ዘኍል. ፲፬ ፥ ፴፫ ፤ መዝ. ፺፭ ፥ ፱ ፤ ፲ ። ፲፱ ፤ ዘዳግ. ፯ ፥ ፩ ፤ ኢያ. ፲፬ ፥ ፩ ፤ ፪ ። ፳ ፤ መሳ. ፪ ፥ ፲፮ ። ፳፩ ፤ ፩ ሳሙ. ፰ ፥ ፭ ፤ ፲ ፥ ፩ ፤ ፳፩ ፤ ፳፬ ። ፳፪ ፤ ፩ ሳሙ. ፲፭ ፥ ፳፫ ፤ ፲፮ ፥ ፩ ፤ ፲፫ ፤ ፲፫ ፥ ፲፬ ፤ መዝ. ፹፱ ፥ ፳ ። ፳፫ ፤ ኢሳ. ፲፩ ፥ ፩ ። ፳፬ ፤ ማር. ፩ ፥ ፬ ።

ራኤል ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ የንስሐን ፡ ጥምቀት ፡ ሰብኮ ፡ ነበር ። ዮሐንስም ፡ ሩጫውን ፡ ሲፈ

፳፭ ጽም ፡ ሳለ ፡— እኔ ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ታስባላችሁ ? እኔስ ፡ እርሱን ፡ አይደለሁም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እነሆ ÷ የእግሩን ፡ ጫማ ፡ እፈታ ፡ ዘንድ ፡ ከማይገባኝ ፡ ከእኔ ፡ በኋላ ፡ ይመጣል ፡ ይል ፡ ነበር ።

፳፮ እናንተ ፡ ወንድሞቻችን ÷ የአብርሃም ፡ ዘር ፡ ልጆች ፡ ከእናንተ ፡ መካከልም ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩ ፡ ሆይ ÷ ለእናንተ ፡ የዚህ ፡ የመ

፳፯ ዳን ፡ ቃል ፡ ተላከ ። በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎችና ፡ አለቆቻቸው ፡ እርሱንና ፡ በየሰንበቱ ፡ የሚነበቡትን ፡ የነቢያትን ፡ ድምፆች ፡ ስላላወቁ ፡

፳፰ በፍርዳቸው ፡ ፈጽመዋልና ፤ ለሞትም ፡ የሚያደርስ ፡ ምክንያት ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ ባያገኙበት ÷ ይገድሉት ፡ ዘንድ ፡ ጲላጦስን ፡ ለመኑት ፤

፳፱ ስለ ፡ እርሱም ፡ የተጻፈውን ፡ ሁሉ ፡ በፈጸሙ ፡ ጊዜ ፡ ከእንጨት ፡ አውርደው ፡ በመቃብር ፡ አኖ

፴ ሩት ። እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ከሙታን ፡ አስነ

፴፩ ሣው ፤ በሕዝብም ፡ ዘንድ ፡ ምስክሮቹ ፡ ለሆኑት ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ከገሊላ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡

፴፪ ለወጡት ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ ታያቸው ። እኛም ፡ ለአባቶች ፡ የተሰጠውን ፡ ተስፋ ፡ የምስራቹን ፡ ለእ

፴፫ ናንተ ፡ እንሰብክለን ፤ ይህን ፡ ተስፋ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሁለተኛው ፡ መዝሙር ፡ ደግሞ ፡—

አንተ ፡ ልጄ ፡ ነህ ÷ እኔ ፡ ዛሬ ፡ ወለድሁህ ፡

ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ÷ ኢየሱስን ፡ አስነሥቶ ፡

፴፬ ለእኛ ፡ ለልጆቻቸው ፡ ፈጽሞአልና ። እንደ ፡ ገናም ፡ ወደ ፡ መበስበስ ፡ እንዳይመለስ ፡ ከሙታን ፡ እንደ ፡ አስነሣው ÷ እንዲህ ፡— የታመነውን ፡ የዳዊትን ፡ ቅዱስ ፡ ተስፋ ፡ እሰጣችኋለሁ ፡

፴፭ ብሎአል ። ደግሞ ፡ በሌላ ፡ ስፍራ ፡— ቅዱስህን ፡ መበስበስን ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ አትሰጠውም ፡

፴፮ ይላልና ። ዳዊትም ፡ በራሱ ፡ ዘመን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ አሳብ ፡ ካገለገለ ፡ በኋላ ፡ አንቀላፋ ÷ ከአባቶቹም ፡ ጋር ፡ ተጨምሮ ፡ መበስበስን ፡ አየ ፤

፴፯ ይህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያስነሣው ፡ ግን ፡ መበሰበ

፴፰፡፴፱ ስን ፡ አላየም ። እንግዲህ ፡ ወንድሞች ፡ ሆይ ፡ በእርሱ ፡ በኩል ፡ የኃጢአት ፡ ስርየት ፡ እንዲነገርላችሁ ÷ በሙሴም ፡ ሕግ ፡ ትጸድቁበት ፡ ዘንድ ፡ ከማይቻላችሁ ፡ ሁሉ ፡ ያመነ ፡ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ እንዲጸድቅ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ የታወቀ ፡ ይሁን ።

፵፡፵፩ እንግዲህ ፡—

እናንተ ፡ የምትንቁ ÷ እዩ ፡ ተደነቁም ፡ ጥፉም ፤ አንድ ፡ ስንኳ ፡ ቢተርክላችሁ ፡ የማታምኑትን ፡ ሥራ ፡ በዘመናችሁ ፡ እኔ ፡ እሠራለሁና ፡

ተብሎ ፡ በነቢያት ፡ የተነገረው ፡ እንዳይደርስባችሁ ፡ ተጠንቀቁ ።

፵፪ በወጡም ፡ ጊዜ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ በሚመጣው ፡ ሰንበት ፡ ይነግሩአቸው ፡ ዘንድ ፡ ለመኑአቸው ።

፵፫ ጉባኤውም ፡ ከተፈታ ፡ በኋላ ፡ ከአይሁድና ፡ ወደ ፡ ይሁዲነት ፡ ገብተው ፡ ከሚያመልኩ ፡ ብዙዎች ፡ ጳውሎስንና ፡ በርናባስን ፡ ተከተሉአቸው ÷ እነርሱም ፡ ሲነግሩአቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ ጸንተው ፡ እንዲኖሩ ፡ አስረዱአቸው ።

፵፬ በሁለተኛውም ፡ ሰንበት ፡ ከጥቂቶቹ ፡ በተር ፡ የከተማው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡

፵፭ ቃል ፡ ይሰሙ ፡ ዘንድ ፡ ተሰበሰቡ ። አይሁድም ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ቅንዓት ፡ ሞላባቸው ÷ እየ ተሳደቡም ፡ ጳውሎስ ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ ተቃ

፵፮ ወሙ ። ጳውሎስና ፡ በርናባስም ፡ ገልጠው ፡— የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ አስቀድሞ ፡ ለእናንተ ፡ ይነገር ፡ ዘንድ ፡ ያስፈልጋል ፤ ከገፋችሁትና ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ እንዳይገባችሁ ፡ በራሳችሁ ፡ ከፈረዳችሁ ፡ ግን ÷ እነሆ ÷ ወደ ፡ አሕዛብ ፡ ዘወር ፡

፵፯ እንላለን ። እንዲሁ ፡ ጌታ ፡—

እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ለማዳን ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ለአሕዛብ ፡ ብርሃን ፡ አድርጌሃለሁ ፡

ብሎ ፡ አዝዞናል ፡ አሉ ።

፵፰ አሕዛብም ፡ ሰምተው ፡ ደስ ፡ አላቸው ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ቃል ፡ አከበሩ ÷ ለዘላለም ፡ ሕይ

፵፱ ወትም ፡ የተዘጋጁ ፡ ሁሉ ፡ አመኑ ፤ የጌታም ፡

፶ ቃል ፡ በአገሩ ፡ ሁሉ ፡ ተሰፋፋ ። አይሁድ ፡ ግን ፡ የሚያመልኩትን ፡ የከበሩትንም ፡ ሴቶችና ፡ የከተማውን ፡ መኳንንት ፡ አወኩ ÷ በጳውሎስና ፡ በበርናባስም ፡ ላይ ፡ ስደትን ፡ አስነሥተው ፡ ከአ

፶፩ ገራቸው ፡ አወጡአቸው ። እነርሱ ፡ ግን ፡ የእግራቸውን ፡ ትቢያ ፡ አራግፈውባቸው ፡ ወደ ፡

፶፪ ኢቆንዮን ፡ መጡ ። በደቀ ፡ መዛሙርትም ፡ ደስታና ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሞላባቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ በኢቆንዮንም ፡ እንደ ፡ ቀድሞ ፡ ወደ ፡ አይሁድ ፡ ምኵራብ ፡ ገብተው ፡ ከአይሁድና ፡ ከግሪክ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ እስኪያምኑ ፡ ድረስ ፡ ተናገሩ ።

፪ ያላመኑት ፡ አይሁድ ፡ ግን ፡ የአሕዛብን ፡ ልብ ፡

፫ በወንድሞች ፡ ላይ ፡ አነሣሡ ፡ አስከፉም ። ምልክትና ፡ድንቅ ፡ በእጃቸው ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ እየሰጠ ፡ ለጸጋው ፡ ቃል ፡ ስለ ፡ መሰከረው ፡ ስለ ፡ ጌታ ፡ ገልጠው ፡ እየተናገሩ ፡ ረጅም ፡ ወራት ፡

፬ ተቀመጡ ። የከተማውም ፡ ሕዝብ ፡ ተከፍለው ፡ እኵሌቶቹ ፡ ከአይሁድ ፡ እኵሌቶቹም ፡ ከሐዋር

፭ ያት ፡ ጋር ፡ ሆኑ ። አሕዛብና ፡ አይሁድ ፡ ግን ፡ ከአለቆቻቸው ፡ ጋር ፡ ሊያንገላቱአቸውና ፡ ሊወ

፮ ግሩአቸው ፡ ባሰቡ ፡ ጊዜ ÷ አውቀው ፡ ልስጥራንና ፡ ደርቤን ፡ ወደሚባሉት ፡ ወደ ፡ ሊቃኦንያ ፡

፲፫ ። ፳፭ ፤ ዮሐ. ፩ ÷ ፳ ፡ ፳፯ ። ፳፯ ፤ ም. ፫ ÷ ፲፯ ፤ ዮሐ. ፲፮ ÷ ፫ ። ፳፰ ፤ ሉቃ. ፳፫ ÷ ፳፱ ፡ ፳፫ ። ፳፱ ፤ ዮሐ. ፲፱ ÷ ፳፰—፴ ፤ ፴፰ ፴፩ ፡ ፴—፴፯ ። ፴፩ ፤ ም. ፩ ÷ ፫ ። ፴፫ ፤ መዝ. ፪ ÷ ፯ ። ፴፬ ፤ ኢሳ. ፶፭ ÷ ፫ ። ፴፭ ፤ መዝ. ፲፭ ÷ ፲ ። ፴፰ ፤ ም. ፪ ÷ ፴፱ ። ፴፰ ፤ ሉቃ. ፳፬ ÷ ፵፯ ። ፵፩ ፤ ዕንባ. ፩ ÷ ፭ ። ፵፯ ፤ ም. ፩ ÷ ፰ ፤ ማቴ. ፲ ÷ ፭ ፤ ፳፭ ÷ ፵፫ ። ፵፯ ፤ ኢሳ. ፵፱ ÷ ፮ ። ፵፰ ፤ ሮሜ. ፰ ÷ ፳፱ ፡ ፴ ። ፶፩ ፤ ሉቃ. ፱ ÷ ፭ ።

፲፬ ። ፮ ፤ ማቴ. ፲ ÷ ፳፫ ።

ከተማዎች ፡ በእነርሱም ፡ ዙሪያ ፡ ወዳለው ፡ አገር ፡ ፯ ሸሹ ፤ በዚያም ፡ ወንጌልን ፡ ይሰብኩ ፡ ነበር ።

፰ በልስጥራንም ፡ እግሩ ፡ የሰለለ ፥ ከእናቱም ፡ ማኅፀን ፡ ጀምሮ ፡ አንካሳ ፡ የሆነ ፥ ከቶም ፡ ሄዶ ፡ የማያውቅ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ። ፱ ይህም ፡ ሰው ፡ ጳውሎስ ፡ ሲናገር ፡ ይሰማ ፡ ነበር ፤ እርሱም ፡ ትኵር ፡ ብሎ ፡ ተመለከተውና ፡ ይድን ፡ ፲ ዘንድ ፡ እምነት ፡ እንዳለው ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፥ በታላቅ ፡ድምፅ ፡— ቀጥ ፡ ብለህ ፡ በእግርህ ፡ ቁም ፡ አለው ። ብድግ ፡ ብሎም ፡ ተነሥቶ ፡ ይመላለስ ፡ ፲፩ ነበር ። ሕዝቡም ፡ ጳውሎስ ፡ ያደረገውን ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ድምፃቸውን ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡ በሊቃኦንያ ፡ ቋንቋ ፡— አማልክት ፡ ሰዎችን ፡ መስለው ፡ ፲፪ ወደ ፡ እኛ ፡ ወርደዋል ፡ አሉ ፤ በርናባስንም ፡ ድያ ፡ አሉት ፤ ጳውሎስንም ፡ እርሱ ፡ በመናገር ፡ ፲፫ ዋና ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ሄርሜን ፡ አሉት ። በከተማውም ፡ ፊት ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ያለው ፡ የድያ ፡ ካህን ፡ ኮርማዎችንና ፡ የአበባን ፡ አክሊሎች ፡ ወደ ፡ ደጃፍ ፡ አምጥቶ ፡ ከሕዝቡ ፡ ጋር ፡ ሆኖ ፡ ሊሠ ፲፬ ዋላቸው ፡ ወደደ ። ሐዋርያት ፡ በርናባስና ፡ ጳውሎስ ፡ ግን ፡ ይህን ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ልብሳቸውን ፡ ቀደው ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ መካከል ፡ እየጮኹ ፡ ፲፭ ሮጡ ፥ እንዲህም ፡ አሉ ፡— እናንተ ፡ ሰዎች ፥ ይህን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ታደርጋላችሁ ? እኛ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ እናንተ ፡ የምንሰማ ፡ ሰዎች ፡ነን ፥ ከዚህም ፡ ከንቱ ፡ነገር ፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ ባሕርንም ፡ በእነርሱም ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ፈጠረ ፡ ወደ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘወር ፡ ትሉ ፡ ፲፮ ዘንድ ፡ ወንጌልን ፡ እንሰብካለን ። እርሱ ፡ ባለፉት ፡ ትውልዶች ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ በገዛ ፡ ራሳ ፲፯ ቸው ፡ ጐዳና ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ተዋቸው ። ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ እየሠራ ፥ ከሰማይ ፡ ዝናብን ፡ ፍሬ ፡ የሚሆንበትንም ፡ወራት ፡ ሲሰጠን ፥ ልባችንንም ፡ በመብልና ፡ በደስታ ፡ ሲሞላው ፡ ራሱን ፡ ያለ ፡ ምስክር ፡ አልተወም ። ፲፰ ይህንም ፡ ብለው ፡ እንዳይሠዉላቸው ፡ ሕዝቡን ፡ በጭንቅ ፡ አስተዉአቸው ።

፲፱ አይሁድ ፡ ግን ፡ ከአንጾኪያና ፡ ከኢቆንዮን ፡ መጡ ፤ ሕዝቡንም ፡ አባብለው ፡ ጳውሎስን ፡ ወገሩ ፡ የሞተም ፡ መስሎአቸው ፡ ከከተማ ፡ ወደ ፡ ፳ ውጭ ፡ ጐተቱት ። ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ግን ፡ ከበውት ፡ ሳሉ ፥ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ገባ ። በነገውም ፡ ከበርናባስ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ደርቤን ፡ ፳፩፳፪ ወጣ ። በዚያችም ፡ ከተማ ፡ ወንጌልን ፡ ሰብከው ፡ እጅግ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርትን ፡ ካደረጉ ፡ በኋላ ፥ የደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ ልብ ፡ እያጸኑ ፡ በሃይማኖትም ፡ ጸንተው ፡ እንዲኖሩ ፡ እየመከሩና ፡— ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ በብዙ ፡ መከራ ፡ እንገባ ፡ ዘንድ ፡ ያስፈልገናል ፡ እያሉ ፥ ወደ ፡ ልስጥራን ፡ ወደ ፡ ኢቆንዮንም ፡ ፳፫ ወደ ፡ አንጾኪያም ፡ ተመለሱ ። በየቤተ ፡ ክርስቲያኑም ፡ ሽማግሌዎችን ፡ ከሾሙላቸው ፡ በኋላ ፡ ጦመውም ፡ ከጸለዩ ፡ በኋላ ፥ ላመኑበት ፡ ለጌታ ፡ አደራ ፡ ሰጡአቸው ።

፳፬ በጲስድያም ፡ አልፈው ፡ ወደ ፡ ጵንፍልያ ፡ ፳፭ መጡ ፥ በጴርጌንም ፡ ቃሉን ፡ ከተናገሩ ፡ በኋላ ፡ ፳፮ ወደ ፡ አጣልያ ፡ ወረዱ ፥ ከዚያም ፡ ስለ ፡ ፈጸሙት ፡ ሥራ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ አደራ ፡ ወደ ፡ ተሰጡበት ፡ ወደ ፡ አንጾኪያ ፡ በመርከብ ፡ ፳፯ ሄዱ ። በደረሱም ፡ ጊዜ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያኑን ፡ ሰብስበው ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፡ ለአሕዛብም ፡ የሃይማኖትን ፡ ደጅ ፡ እንደ ፡ ከፈተላቸው ፡ ተናገሩ ። ፳፰ ከደቀ ፡ መዛሙርትም ፡ ጋር ፡ አያሌ ፡ ቀን ፡ ተቀመጡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ አንዳንዶችም ፡ ከይሁዳ ፡ ወረዱና ፡— እንደ ፡ ሙሴ ፡ ሥርዓት ፡ ካልተገረዛችሁ ፡ ትድኑ ፡ ዘንድ ፡ አትችሉም ፡ ብለው ፡ ወንድሞችን ፡ ያስተምሩ ፡ ፪ ነበር ። በእነርሱና ፡ በጳውሎስ ፡ በበርናባስም ፡ መካከል ፡ ብዙ ፡ ጥልና ፡ ክርክር ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፥ ስለዚህ ፡ ክርክር ፡ ጳውሎስና ፡ በርናባስ ፡ ከእነርሱም ፡ አንዳንዶች ፡ ሌሎች ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ሐዋርያት ፡ ወደ ፡ ሽማግሌዎችም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ፫ ይወጡ ፡ ዘንድ ፡ ተቈረጠ ። ቤተ ፡ ክርስቲያኑም ፡ በመንገድ ፡ እየረዳቸው ፡ እነርሱ ፡ የአሕዛብን ፡ መመለስ ፡ እየተረኩ ፡ በፊንቄና ፡ በሰማርያ ፡ አለፉ ፥ ወንድሞችንም ፡ ሁሉ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አሰኙአቸው ። ፬ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ በደረሉ ፡ ጊዜ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንና ፡ ሐዋርያት ፡ ሽማግሌዎችም ፡ ተቀበሉአቸው ፥ እግዚአብሔርም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፡ አወሩ ። ፭ ከፈሪሳውያን ፡ ወገን ፡ ግን ፡ ያመኑት ፡ አንዳንዶቹ ፡ ተነሥተው ፡— ትገርዙአቸው ፡ ዘንድና ፡ የሙሴን ፡ ሕግ ፡ እንዲጠብቁ ፡ ታዙአቸው ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ፡ አሉ ።

፮ ሐዋርያትና ፡ ሽማግሌዎችም ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ለመማከር ፡ ተሰበሰቡ ። ፯ ከብዙ ፡ ክርክርም ፡ በኋላ ፡ ጴጥሮስ ፡ ተነሥቶ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ አሕዛብ ፡ ከአፌ ፡ የወንጌልን ፡ ቃል ፡ሰምተው ፡ያምኑ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመጀመሪያው ፡ ዘመን ፡ ከእናንተ ፡ እኔን ፡ እንደ ፡ መረጠኝ ፡ እናንተ ፡ ታውቃላችሁ ። ፰ ልብንም ፡ የሚያውቅ ፡ አምላክ ፡ ለእኛ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ሰጠን ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ በመስጠት ፡ መሰከረላቸው ፤ ፱ ልባቸውንም ፡ በእምነት ፡ ሲያነጻ ፡ በእኛና ፡ በእነርሱ ፡ መካከል ፡ አንዳች ፡ አልለየም ። ፲ እንግዲህ ፡ አባቶቻችንና ፡ እኛ ፡ ልንሸከመው ፡ ያልቻልነውን ፡ ቀንበር ፡ በደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ጫንቃ ፡ ላይ ፡ በመጫን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አሁን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትፈታተናላችሁ ? ፲፩ ነገር ፡ ግን ፡ በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋ ፡ እንደ ፡

፲፬ ። ፱ ፤ ማቴ. ፱ ፡ ፳፰ ። ፲፭ ፤ ሐሥ. ፲፬ ፡ ፳፮ ። ፲፯ ፤ መዝ. ፻፵፯ ፡ ፱—፲፫ ። ፳፪ ፤ ማቴ. ፲፮ ፡ ፳፬ ፤ ሉቃ. ፳፬ ፡ ፳፮ ፤ ፳፬ ። ፳፯ ፤ ም. ፲፫ ፡ ፩—፫ ።

፲፭ ። ፩ ፤ ዘሌዋ. ፲፪ ፡ ፫ ። ፯ ፤ ም. ፲፩ ፡ ፲፱—፲፰ ። ፲ ፤ ሉቃ. ፲፩ ፡ ፵፮ ፤ ገላ. ፫ ፡ ፲ ። ፲፩ ፤ ገላ. ፪ ፡ ፲፮ ፤ ኤፌ. ፪ ፡ ፰ ፡ ፱ ።

እነርሱ ፡ ደግሞ ፡ እንድን ፡ ዘንድ ፡ እናምናለን ።

፲፪ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ዝም ፡ አሉ ፥ በርናባስና ፡ ጳውሎስም ፡ እግዚአብሔር ፡ በእጃቸው ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ያደረገውን ፡ ምልክትና ፡ ድንቅ ፡ ሁሉ ፡ ሲተርኩላቸው ፡ ይሰሙ ፡ ነበር ። ፲፫ እነርሱም ፡ ዝም ፡ ካሉ ፡ በኋላ ፡ ያዕቆብ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ መለሰ ፡— ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ስሙኝ ። ፲፬ እግዚአብሔር ፡ ለስሙ ፡ የሚሆንን ፡ ወገን ፡ ከአሕዛብ ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ፡ አስቀድሞ ፡ እንዴት ፡ ፲፭ እንደ ፡ ጐበኘ ፡ ስምዖን ፡ ተርኮአል ። ከዚህም ፡ ጋር ፡ የነቢያት ፡ ቃል ፡ ይስማማል ፥ እንዲህ ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡—

፲፮ ፡ ፲፯ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የቀሩቱ ፡ ሰዎችና ፡ በስሜ ፡ የተጠሩት ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ጌታን ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ፡ እመለሳለሁ ፥ የወደቀችውንም ፡ የዳዊትን ፡ ድንኳን ፡ እንደ ፡ ገና ፡ እሠራታለሁ ፥ ፍራሾዋንም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ እሠራታለሁ ፡ እንደ ፡ ገናም ፡ አቆማታለሁ ፡ ይላል ፡ ይህን ፡ የሚያደርግ ፡ ጌታ ። ፲፰ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ሥራው ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የታወቀ ፡ ነው ።

፲፱ ስለዚህ ፡ ከአሕዛብ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የዞሩ ፳ ትን ፡ እንዳናስቸግራቸው ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ከጣዖት ፡ ርኵሰትና ፡ ከዝሙት ፡ ከታንቀም ፡ ከደምም ፡ ይርቁ ፡ ዘንድ ፡ እንድንጽፍላቸው ፡ እቈርጣለሁ ። ፳፩ ሙሴስ ፡ ከቀድሞ ፡ ትውልድ ፡ ጀምሮ ፡ በሰንበት ፡ በሰንበት ፡ በምኵራቦች ፡ ሲያነቡ ፡ በየከተማው ፡ እርሱን ፡ የሚሰብኩ ፡ አሉት ።

፳፪ ያን ፡ ጊዜ ፡ ሐዋርያትና ፡ ሽማግሌዎች ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ከእነርሱ ፡ የተመረጡትን ፡ ሰዎች ፡ ከጳውሎስና ፡ ከበርናባስ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ አንጾኪያ ፡ ይልኩ ፡ ዘንድ ፡ ፈቀዱ ፤ እነርሱም ፡ በወንድሞች ፡ መካከል ፡ ዋናዎች ፡ የነበሩ ፡ በርስያን ፡ የተባለው ፡ ይሁዳና ፡ ሲላስ ፡ ነበሩ ። ፳፫ እንዲህም ፡ ጽፈው ፡ በእነርሱ ፡ እጅ ፡ ላኩ ፡— ሐዋርያትና ፡ ሽማግሌዎች ፡ ወንድሞችም ፡ በአንጾኪያና ፡ በሶርያ ፡ በኪልቅያም ፡ ለሚኖሩ ፡ ከአሕዛብ ፡ ወገን ፡ ለሆኑ ፡ ወንድሞች ፡ ሰላምታ ፡ ፳፬ ያቀርባሉ ። ያላዘዝናቸው ፡ ሰዎች ፡ ከእኛ ፡ ወጥተው ፡— ትገረዙ ፡ ዘንድና ፡ ሕግን ፡ ትጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ይገባችኋል ፡ ብለው ፡ ልባችሁን ፡ እያወኩ ፡ በቃል ፡ እንዳናወጡአችሁ ፡ ስለ ፡ ሰማን ፥ ፳፭ ፡ ፳፮ ስለ ፡ ጌታችን ፡ ስለ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስም ፡ ነፍሳቸውን ፡ ከሰጡት ፡ ከምንወዳቸው ፡ ከበርናባስና ፡ ከጳውሎስ ፡ ጋር ፡ የተመረጡትን ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ እንልክ ፡ ዘንድ ፡ በአንድ ፡ ልብ ፡ ፳፯ ሆነን ፡ ፈቀድን ። ራሳቸውም ፡ ደግሞ ፡ በቃላቸው ፡ ያንኑ ፡ ያነግሩአችሁ ፡ ዘንድ ፡ ይሁዳንና ፡ ፳፰ ፡ ፳፱ ሲላስን ፡ ልከናል ። ለጣዖት ፡ ከተሠዋ ፥ ከደምም ፥ ከታንቀም ፥ ከዝሙትም ፡ ትርቁ ፡ ዘንድ ፡ ከዚህ ፡ ከሚያስፈልገው ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ሸክም ፡ እንዳንጭንባችሁ ፡ እኛና ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ፈቅደናልና ፤ ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ ራሳችሁን ፡ ብትጠብቁ ፡ በመልካም ፡ ትኖራላችሁ ። ጤና ፡ ይስጣችሁ ።

፴ እነርሱም ፡ ተሰናብተው ፡ ወደ ፡ አንጾኪያ ፡ ወረዱ ፥ ሕዝቡንም ፡ ሰብስበው ፡ ደብዳቤውን ፡ ፴፩ ሰጡአቸው ። ባነበቡትም ፡ ጊዜ ፡ ከምክሩ ፡ የተ ፴፪ ነሣ ፡ ደስ ፡ አላቸው ። ይሁዳና ፡ ሲላስም ፡ ደግሞ ፡ ነቢያት ፡ ነበሩና ፡ ወንድሞችን ፡ በብዙ ፡ ቃል ፡ ፴፫ መከረው ፡ አጸኑአቸው ። አያሌ ፡ ቀንም ፡ ከተቀመጡ ፡ በኋላ ፡ ከወንድሞች ፡ በሰላም ፡ ተሰናብተው ፡ ወደ ፡ ሐዋርያት ፡ ሄዱ ። ፴፬ ሲላስ ፡ ግን ፡ ፴፭ በዚያ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ ፈቀደ ። ጳውሎስና ፡ በርናባስም ፡ ከሌሎች ፡ ከብዙ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ደግሞ ፡ የጌታን ፡ ቃል ፡ እያስተማሩና ፡ ወንጌልን ፡ እየሰበኩ ፡ በአንጾኪያ ፡ ይቀመጡ ፡ ነበር ።

፴፮ ከጥቂት ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ጳውሎስ ፡ በርናባስን ፡— ተመልሰን ፡ የጌታን ፡ ቃል ፡ በተናገርንበት ፡ በየከተማው ፡ ሁሉ ፡ ወንድሞችን ፡ እንጐብኛቸው ፥ እንዴት ፡ እንዳሉም ፡ እንወቅ ፡ ፴፯ አለው ። በርናባስም ፡ ማርቆስ ፡ የተባለውን ፡ ዮሐንስን ፡ ደግሞ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ይወስድ ፡ ፴፰ ዘንድ ፡ አሰበ ፤ ጳውሎስ ፡ ግን ፡ ይህን ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ሊወስድ ፡ አልፈቀደም ፥ ከእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ከጵንፍልያ ፡ ተለይቶ ፡ ነበርና ፥ ወደ ፡ ሥራም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ አልመጣም ፡ ፴፱ ነበርና ። ስለዚህም ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ እስኪለያዩ ፡ ድረስ ፡ መከፋፋት ፡ ሆነ ፥ በርናባስም ፡ ማርቆስን ፡ ይዞ ፡ በመርከብ ፡ ወደ ፡ ቆጵሮስ ፡ ፵ ሄደ ። ጳውሎስ ፡ ግን ፡ ሲላስን ፡ መረጠ ፥ ወንድሞችም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ አደራ ፡ ከሰ ፵፩ ጡት ፡ በኋላ ፡ ወጣ ፤ አብያተ ፡ ክርስቲያናትንም ፡ እያጸና ፡ በሶርያና ፡ በኪልቅያ ፡ ይዞር ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ ወደ ፡ ደርቤንና ፡ ወደ ፡ ልስጥራንም ፡ ደረሰ ። እነሆም ፥ በዚያ ፡ የአንዲት ፡ ያመነች ፡ አይሁዳዊት ፡ ልጅ ፡ ጢሞቴዎስ ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ነበረ ፤ አባቱ ፡ ግን ፡ የግሪክ ፡ ሰው ፡ ፪ ነበረ ። ለእርሱም ፡ በልስጥራንና ፡ በኢቆንዮን ፡ ፫ ያሉ ፡ ወንድሞች ፡ መሰከሩለት ። ጳውሎስ ፡ ይህ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይወጣ ፡ ዘንድ ፡ ወደደ ፥ በእነዚያም ፡ ስፍራዎች ፡ ስለ ፡ ነበሩ ፡ አይሁድ ፡ ይዞ ፡ ገረዘው ፤ አባቱ ፡ የግሪክ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ፬ ሆነ ፡ ሁሉ ፡ ያውቁ ፡ ነበርና ። በከተማዎችም ፡ ሲዞሩ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የነበሩት ፡ ሐዋርያትና ፡ ሽማግሌዎች ፡ የቈረጡትን ፡ ሥርዓት ፡ ይጠብቁ ፡ ፭ ዘንድ ፡ ሰጡአቸው ። አብያተ ፡ ክርስቲያናትም ፡ በሃይማኖት ፡ ይበረቱ ፡ ነበር ፥ በቍጥርም ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ይበዙ ፡ ነበር ።

፲፭ ። ፲፮ ፡ ፲፯ ፡ ዓሞ. ፱ ፥ ፲፩ ፡ ፲፪ ። ፳ ፤ ፩ ቆሮ. ፲ ፥ ፳ ፡ ፳ ፡ ፳፩ ፤ ዘፍ. ፱ ፥ ፬ ። ፳፩ ፤ ምዕ. ፲፫ ፥ ፲፭ ። ፳፰ ፤ ምዕ. ፲፩ ፥ ፱ ። ፴፰ ፤ ምዕ. ፲፫ ፥ ፲፫ ።
፲፮ ። ፩ ፤ ፪ ጢሞ. ፩ ፥ ፭ ። ፫ ፤ ምዕ. ፲፭ ፥ ፳፰ ፡ ፳፱ ።

፮ በእስያም ፡ ቃሉን ፡ እንዳይናገሩ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ስለ ፡ ከለከላቸው ፡ በፍርግያና ፡ በገላትያ ፡ ፯ አገር ፡ አለፉ ፤ በሚስያም ፡ አንጻር ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ቢታንያ ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ሞከሩ ÷ የኢየሱስ ፡ መንፈስም ፡ አልፈቀደላቸውም ፤ ፰ በሚስያም ፡ አጠገብ ፡ አልፈው ፡ ወደ ፡ ጢሮአዳ ፡ ፱ ወረዱ ። ራእይም ፡ ለጳውሎስ ፡ በሌሊት ፡ ታየው ፤ አንድ ፡ የመቄዶንያ ፡ ሰው ፡— ወደ ፡ መቄዶንያ ፡ ተሻገርና ፡ እርዳን ፡ እያለ ፡ ቆሞ ፡ ፲ ሲለምነው ፡ ነበር ። ራእዩንም ፡ ካየ ፡ በኋላ ፡ ወዲያው ፡ ወደ ፡ መቄዶንያ ፡ ልንወጣ ፡ ፈለግን ÷ ወንጌልን ፡ እንሰብክላቸው ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ጠራን ፡ መስሎናልና ።

፲፩ ከጢሮአዳም ፡ ተነሥተን ፡ በቀጥታ ፡ ወደ ፡ ሳሞትራቄ ፡ በነገውም ፡ ወደ ፡ ናጱሌ ፡ በመር ፲፪ከብ ፡ ሄድን ፤ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ፊልጵስዩስ ፡ ደረስን ፤ እርስዋም ፡ የመቄዶንያ ፡ ከተማ ፡ ሆና ÷ የወረዳ ፡ ዋና ፡ ከተማና ፡ ቅኝ ፡ አገር ፡ ናት ፤ በዚህችም ፡ ከተማ ፡ አንዳንድ ፡ ቀን ፡ እንቀመጥ ፡ ፲፫ ነበር ። በሰንበት ፡ ቀንም ፡ ከከተማው ፡ በር ፡ ውጭ ፡ የጸሎት ፡ ስፍራ ፡ በዚያ ፡ መሆኑን ፡ ስላ ሰብን ፡ ወደ ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ ወጣን ፤ ተቀም ፲፬ጠንም ፡ ስተሰበሰቡት ፡ ሴቶች ፡ ተናገርን ። ከት ያጥሮን ፡ ከተማም ፡ የመጣች ፡ ቀይ ፡ ሐር ፡ ሻጭ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምታመልክ ፡ ልድያ ፡ የሚሉአት ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ትሰማ ፡ ነበረች ፤ ጳውሎስም ፡ የሚናገረውን ፡ ታዳምጥ ፡ ዘንድ ፡ ጌታ ፡ ፲፭ ልብዋን ፡ ከፈተላት ። እርስዋም ፡ ከቤተ ፡ ሰዎችዋ ፡ ጋር ፡ ከተጠመቀች ፡ በኋላ ፡— በጌታ ፡ የማምን ፡ እንድሆን ፡ ከፈረዳችሁልኝ ÷ ወደ ፡ ቤቴ ፡ ገብታችሁ ፡ ኑሩ ፡ ብላ ፡ ለመነችን ፤ በግድም ፡ አለችን ።

፲፮ ወደ ፡ ጸሎት ፡ ስፍራም ፡ ስንሄድ ÷ የምዋርተኝነት ፡ መንፈስ ፡ የነበረባት ፡ ለጌቶችዋም ፡ እየ ጠንቈለች ፡ ብዙ ፡ ትርፍ ፡ ታመጣ ፡ የነበረች ፡ ፲፯ አንዲት ፡ ገረድ ፡ አገኘችን ። እርስዋ ፡ ጳውሎስንና ፡ እኛን ፡ እየተከተለች ፡— የመዳንን ፡ መንገድ ፡ የሚነግሩአችሁ ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ የልዑል ፡ አምላክ ፡ ባሪያዎች ፡ ናቸው ፡ ብላ ፡ ትጮኽ ፡ ፲፰ ነበር ። ይህንም ፡ እጅግ ፡ ቀን ፡ አደረገች ። ጳውሎስ ፡ ግን ፡ ተቸገረና ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ መንፈሱን ፡— ከእርስዋ ፡ እንድትወጣ ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስም ፡ እዝዝሃለሁ ፡ አለው ፤ በዚያም ፡ ሰዓት ፡ ወጣ ።

፲፱ ጌቶችዋም ፡ የትርፋቸው ፡ ተስፋ ፡ እንደ ፡ ወጣ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ጳውሎስንና ፡ ሲላስን ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ገበያ ፡ በሹማምት ፡ ፊት ፡ ጐተቱአቸው ፤ ፳ ወደ ፡ ገዢዎችም ፡ አቅርበው ፡— እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ አይሁድ ፡ ሆነው ፡ ከተማችንን ፡ እጅግ ፡ ያናው ፳፩ጣሉ ። እኛም ፡ የሮሜ ፡ ሰዎች ፡ ሆነን ፡ እንቀ በላቸውና ፡ እናደርጋቸው ፡ ዘንድ ፡ ያልተፈቀ ፳፪ደልንን ፡ ልማዶች ፡ ይናገራሉ ፡ አሉ ። ሕዝቡም ፡ አብረው ፡ ተነሡባቸው ÷ ገዢዎቹም ፡ ልብሳቸውን ፡ ገፈው ፡ በበትር ፡ ይመቱአቸው ፡ ዘንድ ፡ ፳፫ አዘዙ ፤ በብዙም ፡ ከደበደቡአቸው ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ወኅኒ ፡ ጣሉአቸው ÷ የወኅኒውንም ፡ ጠባቂ ፡ ፳፬ ተጠንቅቆ ፡ እንዲጠብቃቸው ፡ አዘዙት ። እርሱም ፡ የዚህን ፡ ዓይነት ፡ ትእዛዝ ፡ ተቀብሎ ፡ ወደ ፡ ውስጠኛው ፡ ወኅኒ ፡ ጣላቸው ÷ እግራቸውንም ፡ በግንድ ፡ አጣብቆ ፡ ጠረቃቸው ።

፳፭ በመንፈቀ ፡ ሌሊት ፡ ግን ፡ ጳውሎስና ፡ ሲላስ ፡ እየጸለዩ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በዜማ ፡ ያመሰግኑ ፡ ነበር ÷ እስረኞቹም ፡ ያደምጡአቸው ፡ ነበር ፡ ፳፮ ድንገትም ፡ የወኅኒው ፡ መሠረት ፡ እስኪናወጥ ፡ ድረስ ፡ ታላቅ ፡ የምድር ፡ መንቀጥቀጥ ፡ ሆነ ፡ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ደጆቹ ፡ ሁሉ ፡ ተከፈቱ ፡ የሁ ፳፯ሉም ፡ እስራት ፡ ተፈታ ። የወኅኒውም ፡ ጠባቂ ፡ ከእንቅልፉ ፡ ነቅቶ ፡ የወኅኒው ፡ ደጆች ፡ ተከፍተው ፡ በየ ፡ ጊዜ ÷ እስረኞቹ ፡ ያመለጡ ፡ መስሎት ፡ ራሱን ፡ ይገድል ፡ ዘንድ ፡ እሰበ ፡ ሰይፉን ፡ ፳፰ መዘዘ ። ጳውሎስ ፡ ግን ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡— ሁላችን ፡ ከዚህ ፡ አለንና ፡ በራስህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ፳፱ አታድርግ ፡ ብሎ ፡ ጮኸ ። መብራትም ፡ ለምኖ ፡ ወደ ፡ ውስጥ ፡ ሮጠ ÷ እየተንቀጠቀጠም ፡ ከጳውሎስና ፡ ከሲላስ ፡ ፊት ፡ ተደፋ ፤ ወደ ፡ ውጭም ፡ ፴ አውጥቶ ፡— ጌቶች ፡ ሆይ ÷ እድን ፡ ዘንድ ፡ ምን ፡ ፴፩ ማድረግ ፡ ይገባኛል ? አላቸው ። እነርሱም ፡— በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እመን ፡ አንተና ፡ ፴፪ ቤተ ፡ ሰዎችህም ፡ ትድናላችሁ ፡ አሉት ። ለእርሱና ፡ በቤቱም ፡ ላሉት ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ተናገሩአቸው ። ፴፫ በሌሊትም ፡ በዚያች ፡ ሰዓት ፡ ወስዶ ፡ ቍስላቸውን ፡ አጠበላቸው ÷ ያን ፡ ጊዜውንም ፡ እርሱ ፡ ከቤተ ፡ ሰዎቹ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ተጠመቀ ፤ ፴፬ ወደ ፡ ቤቱም ፡ አውጥቶ ፡ ማዕድ ፡ አቀረበላቸው ÷ በእግዚአብሔርም ፡ ስላመነ ፡ ከቤተ ፡ ሰዎቹ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ሐሤት ፡ አደረገ ።

፴፭ በነጋም ፡ ጊዜ ፡ ገዢዎቹ ፡— እነዚያን ፡ ሰዎች ፡ ፍታቸው ፡ ብለው ፡ ሎሌዎቻቸውን ፡ ላኩ ። ፴፮ የወኅኒውም ፡ ጠባቂ ፡— ትፈቱ ፡ ዘንድ ፡ ገዢዎቹ ፡ ልከዋል ፤ እንግዲህ ፡ አሁን ፡ ወጥታችሁ ፡ በሰላም ፡ ሂዱ ፡ ብሎ ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ለጳውሎስ ፡ ፴፯ ነገረው ። ጳውሎስ ፡ ግን ፡— እኛ ፡ የሮሜ ፡ ሰዎች ፡ ስንሆን ፡ ያለ ፡ ፍርድ ፡ በሕዝብ ፡ ፊት ፡ ደብድበው ፡ በወኅኒ ፡ ጣሉን ፤ አሁንም ፡ በስውር ፡ ይጥሉናልን ? አይሆንም ፤ ራሳቸው ፡ ፴፰ ግን ፡ መጥተው ፡ ያውጡን ፡ አላቸው ። ሎሌዎቹም ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ለገዢዎች ፡ ነገሩ ። የሮሜ ፡ ሰዎችም ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ፈሩ ፤ ፴፱ መጥተውም ፡ ማለዱአቸው ÷ አውጥተውም ፡ ፵ ከከተማ ፡ ይወጡ ፡ ዘንድ ፡ ለመኑአቸው ። ከወኅኒውም ፡ ወጥተው ፡ ወደ ፡ ልድያ ፡ ቤት ፡ ገቡ ÷ ወንድሞችንም ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ አጽናኑአቸውና ፡ ሄዱ ።

፲፮ ። ፩ ፡ ፮ ፤ ም. ፳ ÷ ፳፱ ። ፲፱ ፤ ዮሐ. ፮ ÷ ፶፩ ። ፲፯ ፤ ማር. ፩ ÷ ፯ ። ፴፩ ፤ ም. ፲፩ ÷ ፲፬ ፤ ዮሐ. ፫ ÷ ፲፮ ። ፴፯ ፤ ም. ፳፪ ÷ ፳፭ ። ፴፱ ፤ ማቴ. ፰ ÷ ፴፬ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩፤ በአንፊጶልና ፡ በአጶሎንያም ፡ ካለፉ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ተሰሎንቄ ፡ መጡ ፥ በዚያም ፡ የአይሁድ ፡ ፪፤ ምኵራብ ፡ ነበረ ። ጳውሎስም ፡ እንደ ፡ ልማዱ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ገባ ፥ ሦስት ፡ ሰንበትም ፡ ያህል ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ከመጻሕፍት ፡ እየጠቀሰ ፡ ይነጋ ፫፤ ገር ፡ ነበር ፤ ሊተረጕምም ፡ ክርስቶስ ፡ መከራ ፡ እንዲቀበልና ፡ ከሙታን ፡ እንዲነሣ ፡ ይገባው ፡ ዘንድ ፡ እያስረዳ ፡— ይህ ፡ እኔ ፡ የምሰብካችሁ ፡ ኢየሱስ ፡ እርሱ ፡ ክርስቶስ ፡ ነው ፡ ይል ፡ ነበር ። ፬፤ ከእነርሱም ፡ አንዳንዶቹ ፡ ተረድተው ፥ ከሚያመልኩም ፡ ከግሪክ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ከከበሩትም ፡ ሴቶች ፡ ጥቂቶች ፡ ያይደሉ ፥ ከጳውሎስና ፡ ከሲ ፭፤ ላስ ፡ ጋር ፡ ተባበሩ ። አይሁድ ፡ ግን ፡ ቀንተው ፡ ከሥራ ፡ ፈቶች ፡ ክፉ ፡ ሰዎችን ፡ አመጡ ፡ ሕዝ ብንም ፡ ሰብስበው ፡ ከተማውን ፡ አወኩ ፥ ወደ ፡ ሕዝቡም ፡ ያወጡአቸው ፡ ዘንድ ፡ ፈልገው ፡ ፮፤ ወደ ፡ ኢያሶን ፡ ቤት ፡ ቀረቡ ፤ ባላገኙአቸ ውም ፡ ጊዜ ፡ ኢያሶንንና ፡ ከወንድሞች ፡ አንዳ ንዶችን ፡ ወደ ፡ ከተማው ፡ አለቆች ፡ ጐተተው ፡— ዓለምን ፡ ያወኩ ፡ እነዚህ ፡ ወደዚህ ፡ ደግሞ ፡ ፯፤ መጥተዋል ፥ ኢያሶንም ፡ ተቀብሎአቸዋል ፤ እነዚህም ፡ ሁሉ ፡— ኢየሱስ ፡ የሚሉት ፡ ሌላ ፡ ንጉሥ ፡ አለ ፡ እያሉ ፡ የቄሣርን ፡ ትእዛዝ ፡ ይቃ ፰፤ ወማሉ ፡ ብለው ፡ ጮኹ ። ሕዝቡና ፡ የከተማ ውም ፡ አለቆች ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ፱፤ ታወኩ ፥ ከኢያሶንና ፡ ከሌሎቹም ፡ ዋስ ፡ ተቀብ ለው ፡ ለቀቁአቸው ።

፲፤ ወዲያውም ፡ ወንድሞች ፡ ጳውሎስንና ፡ ሲላ ስን ፡ በሌሊት ፡ ወደ ፡ ቤርያ ፡ ሰደዱአቸው ፥ በደ ረሱም ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ አይሁድ ፡ ምኵራብ ፡ ገቡ ፤ ፲፩፤ እነዚህም ፡ በተሰሎንቄ ፡ ከሚኖሩት ፡ ይልቅ ፡ ልበ ፡ ሰፊዎች ፡ ነበሩና ፡— ነገሩ ፡ እንደዚሁ ፡ ይሆንን ? ብለው ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ መጻሕፍትን ፡ እየመረመሩ ፡ ቃሉን ፡ በሙሉ ፡ ፈቃድ ፡ ተቀ ፲፪፤ በሉ ። ስለዚህም ፡ ከእነርሱ ፡ ብዙ ፥ ከግሪክችም ፡ የከበሩት ፡ ሴቶችና ፡ ወንዶች ፡ ጥቂት ፡ ያይደሉ ፥ ፲፫፤ አመኑ ። በተሰሎንቄ ፡ ያሉት ፡ አይሁድ ፡ ግን ፡ ጳውሎስ ፡ በቤርያ ፡ ደግሞ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ እንደ ፡ ሰበከ ፡ ባወቁ ፡ ጊዜ ፥ ወደዚያው ፡ ፲፬፤ ደግሞ ፡ መጡና ፡ ሕዝቡን ፡ አወኩ ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ወንድሞቹ ፡ ወዲያው ፡ ጳውሎስን ፡ እስከ ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ ሰደዱት ፡ ፲፭፤ ሲላስና ፡ ጢሞቴዎስም ፡ በዚያው ፡ ቀሩ ። ጳው ሎስን ፡ የሸኙት ፡ ግን ፡ እስከ ፡ አቴና ፡ አደረሱት ፥ እንደሚቻላቸውም ፡ በፍጥነት ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ይመጡ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ሲላስና ፡ ወደ ፡ ጢሞቴ ዎስ ፡ ትእዛዝ ፡ ተቀብለው ፡ ሄዱ ።

፲፮፤ ጳውሎስም ፡ በአቴና ፡ ሲጠብቃቸው ፡ ሳለ ፥ በከተማው ፡ ጣዖት ፡ መሙላቱን ፡ እየተመለከተ ፡ ፲፯፤ መንፈሱ ፡ ተበሳጨበት ። ስለዚህም ፡ በምኵ ራብ ፡ ከአይሁድና ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከሚያመ ልኩ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ በየቀኑም ፡ በገበያ ፡ ከሚያ ገኛቸው ፡ ጋር ፡ ይነጋገር ፡ ነበር ። ከኤፊቆሮስ ፡ ፲፰፤ ወገንና ፡ ኢስጦኢኮችም ፡ ከተባሉት ፡ ፈላስፎች ፡ አንዳንዶቹ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተገናኙ ። አንዳን ዶቹም ፡— ይህ ፡ ለፍላፊ ፡ ምን ፡ ሊናገር ፡ ይወ ዳል ? አሉ ፤ ሌሎችም ፡ የኢየሱስንና ፡ የትን ሣኤውን ፡ ወንጌል ፡ ስለ ፡ ሰበካላቸው ፡— እንግዶ ችን ፡ አማልክት ፡ የሚያወራ ፡ ይመስላል ፡ አሉ ። ይዘውም ፡— ይህ ፡ የምትናገረው ፡ አዲስ ፡ ትም ፲፱፤ ህርት ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እናውቅ ፡ ዘንድ ፡ ይቻለናልን ? በጆሮአችን ፡ እንግዳ ፡ ነገር ፡ ታሰ ማናለህና ፤ እንግዲህ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እናውቅ ፡ ዘንድ ፡ እንፈቅዳለን ፡ ብለው ፡ አርዮስፋጎስ ፡ ወደ ፡ ተባለው ፡ ስፍራ ፡ ወሰዱት ። ፳፩፤ የአቴና ፡ ሰዎች ፡ ሁሉና ፡ በዚያ ፡ የኖሩ ፡ እንግ ዶች ፡ አዲስ ፡ ነገርን ፡ ከመናገርና ፡ ከመስማት ፡ በቀር ፡ በሌላ ፡ ጉዳይ ፡ አይውሉም ፡ ነበርና ።

፳፪፤ ጳውሎስም ፡ በአርዮስፋጎስ ፡ መካከል ፡ ቆሞ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡—

የአቴና ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ፥ እናንተ ፡ በሁሉ ፡ ነገር ፡ አማልክትን ፡ እጅግ ፡ እንደምትፈሩ ፡ እመለከ ፳፫፤ ታለሁ ። የምታመልኩትን ፡ እየተመለከትሁ ፡ ሳልፍ ፡— ለማይታወቅ ፡ አምላክ ፡ የሚል ፡ ጽሕ ፈት ፡ ያለበትን ፡ መሠዊያ ፡ ደግሞ ፡ አግኝቼአለ ሁና ። እንግዲህ ፡ ይህን ፡ ሳታውቁ ፡ የምታመል ኩትን ፡ እኔ ፡ እነግራችኋለሁ ። ዓለሙንና ፡ በእ ፳፬፤ ርሱ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ የፈጠረ ፡ አምላክ ፡ እርሱ ፡ የሰማይና ፡ የምድር ፡ ጌታ ፡ነውና ፡ እጅ ፡ በሠራው ፡ መቅደስ ፡ አይኖርም ፤ እርሱም ፡ ሕይወትንና ፡ ፳፭፤ እስትንፋስን ፡ ሁሉንም ፡ ለሁሉ ፡ ይሰጣልና ፡ አን ዳች ፡ እንደሚጐድለው ፡ በሰው ፡ እጅ ፡ አይገለገ ልም ። ምናልባትም ፡ እየመረመሩ ፡ ያገኙት ፡ ፳፮፡፳፯፤ እንደ ፡ ሆነ ፥ እግዚአብሔርን ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እንዲኖሩ ፡ የሰውን ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ ከአንድ ፡ ፈጠረ ፥ የተወሰኑት ንም ፡ ዘመኖችና ፡ ለሚኖሩበት ፡ ስፍራ ፡ ዳርቻ ፡ መደበላቸው ። ቢሆንም ፡ ከእያንዳንዳችን ፡ የራቀ ፡ አይደለም ። ከእናንተ ፡ ከባለ ፡ ቅኔዎች ፡ ፳፰፤ አንዳንዶች ፡ ደግሞ ፡— እኛ ፡ ደግሞ ፡ ዘመዶቹ ፡ ነንና ፡ ብለው ፡ እንደ ፡ ተናገሩ ፥ በእርሱ ፡ ሕያ ዋን ፡ ነንና ፡ እንንቀሳቀሳለን ፡ እንኖርማለን ። እንግዲህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ዘመዶች ፡ ከሆንን ፥ ፳፱፤ አምላክ ፡ በሰው ፡ ብልሃትና ፡ አሳብ ፡ የተቀረጸ ውን ፡ ወርቅ ፡ ወይም ፡ ብር ፡ ወይም ፡ ድንጋይ ፡ እንዲመስል ፡ እናስብ ፡ ዘንድ ፡ አይገባንም ። እንግዲህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያለማወቅን ፡ ወራት ፡ ፴፤ አሳልፎ ፡ አሁን ፡ በየቦታቸው ፡ ንስሐ ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ ያዝል ፡ ቀን ፡ ቀጥሮአ ፴፩፤ ልና ፥ በዚያም ፡ ቀን ፡ ባዘጋጀው ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ በዓለሙ ፡ ላይ ፡ በጽድቅ ፡ ሊፈርድ ፡ አለው ፤

፲፯ ። ፫፤ ሉቃ· ፳፬ ፥ ፳፮ ፡ ፵፮ ። ፯፤ ሉቃ· ፳፫ ፥ ፪ ። ፳፬፤ ዘፍ· ፩ ፥ ፩ — [illegible] ። ፳፬፤ መዝ· ፶፱ ፥ ፰ — ፲፪ ። ፳፮፤ ዘዳግ· ፴፪ ፥ ፰ ፡ ኢዮብ ፲፪ ፥ ፳ ። ፳፰፤ ኢዮብ ፲፪ ፥ ፲ ። ፳፱፤ ኢሳ· ፵ ፥ ፲፰ ። ፴፤ ም· ፲፬ ፥ ፲፮ ፤ ማር· ፩ ፥ ፲፬ ፡ ፲፭ ። ፴፩፤ ም· ፲ ፥ ፵፪ ፡ መዝ· ፺፮ ፥ ፲፫ ።

ስለዚህም ፡ እርሱን ፡ ከሙታን ፡ በማስነሣቱ ፡ ሁሉን ፡ አረጋግጦአል ።

፴፪ የሙታንንም ፡ ትንሣኤ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ አንዳንዶቹ ፡ አፌዙበት ፤ አንዳንዶቹ ፡ ግን ፡— ስለ ዚህ ፡ ነገር ፡ ሁለተኛ ፡ እንሰማሃለን ፡ አሉት ። ፴፫ እንዲሁም ፡ ጳውሎስ ፡ ከመካከላቸው ፡ ወጣ ። ፴፬ አንዳንዶች ፡ ወንዶች ፡ ግን ፡ ተባብረው ፡ አመኑ ፤ ከእነርሱ ፡ ደግሞ ፡ በአርዮስፋጎስ ፡ ያለው ፡ የፍርድ ፡ ቤት ፡ ፈራጅ ፡ ዲዮናስዮስ ፡ ደማሪስ ፡ የሚሉአትም ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ሌሎችም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ነበሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ጳውሎስ ፡ ከአቴና ፡ ወጥቶ ፡ ፪ ወደ ፡ ቆሮንቶስ ፡ መጣ ። በመገኑም ፡ የጳንጦስ ፡ ሰው ፡ የሚሆን ፡ አቂላ ፡ የሚሉትን ፡ አንድ ፡ አይሁዳዊ ፡ አገኘ ፤ እርሱም ፡ ከጥቂት ፡ ጊዜ ፡ በፊት ፡ ከሚስቱ ፡ ከጵርስቅላ ፡ ጋር ፡ ከኢጣልያ ፡ መጥቶ ፡ ነበር ፤ አይሁድ ፡ ከሮሜ ፡ ይወጡ ፡ ዘንድ ፡ ቀላውዴዎስ ፡ አዞ ፡ ነበርና ፤ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ቀረበ ፤ ፫ ሥራቸውም ፡ አንድ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ተቀምጦ ፡ በአንድ ፡ ላይ ፡ ሠሩ ፤ ሥራ ቸው ፡ ድንኳን ፡ መስፋት ፡ ነበረና ። ፬ በየሰንበቱም ፡ ሁሉ ፡ በምኵራብ ፡ ይነጋገር ፡ ነበር ፤ አይሁድንና ፡ የግሪክንም ፡ ሰዎች ፡ ያስረዳ ፡ ነበር ።

፭ ሲላስና ፡ ጢሞቴዎስም ፡ ከመቄዶንያ ፡ በወረዱ ፡ ጊዜ ፤ ጳውሎስ ፡ ኢየሱስ ፡ እርሱ ፡ ክርስቶስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለአይሁድ ፡ እየመሰከረ ፡ ፮ ለቃሉ ፡ ይተጋ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በተቃወሙትና ፡ በተሳደቡ ፡ ጊዜ ፤ ልብሱን ፡ እያራገፈ ፡— ደማችሁ ፡ በራሳችሁ ፡ ነው ፤ እኔ ፡ ንጹሕ ፡ ነኝ ፤ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ወደ ፡ አሕዛብ ፡ እሄዳለሁ ፡ ፯ አላቸው ። ከዚያም ፡ ወጥቶ ፡ ኢዮስጦስ ፡ ወደ ሚባል ፡ እግዚአብሔርን ፡ ወደሚያመልክ ፡ ሰው ፡ ቤት ፡ ገባ ፤ ቤቱም ፡ በምኵራብ ፡ አጠገብ ፡ ነበረ ። ፰ የምኵራብ ፡ አለቃ ፡ ቀርስጶስም ፡ ከቤተ ፡ ሰዎቹ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ በጌታ ፡ አመነ ፤ ከቆሮንቶስ ፡ ሰዎችም ፡ ብዙ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ አምነው ፡ ተጠመቁ ።

፱ ፲ ጌታም ፡ ሌሊት ፡ በራእይ ፡ ጳውሎስን ፡— እኔ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ነኝ ፤ ማንም ፡ ክፉ ፡ ሊያደርግብህ ፡ የሚነሣብህ ፡ የለምና ፡ አትፍራ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ተና ገር ፡ ዝምም ፡ አትበል ፤ በዚህ ፡ ከተማ ፡ ብዙ ፡ ፲፩ ሕዝብ ፡ አሉኝና ፡ አለው ። በመካከላቸውም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ እያስተማረ ፡ ዓመት ፡ ከስድስት ፡ ወር ፡ ተቀመጠ ።

፲፪ ጋልዮስም ፡ በአካይያ ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፤ አይሁድ ፡ በአንድ ፡ ልብ ፡ ሆነው ፡ በጳውሎስ ፡ ላይ ፡ ተነሡ ፤ ወደ ፡ ፍርድ ፡ ወንበርም ፡ ፲፫ አምጥተው ፡— ይህ ፡ ሕግን ፡ ተቃውሞ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመልኩት ፡ ዘንድ ፡ ሰዎችን ፡ ያባብላል ፡ አሉ ። ፲፬ ጳውሎስም ፡ አፉን ፡ ሊከፍት ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፤ ጋልዮስ ፡ አይሁድን ፡— አይሁድ ፡ ሆይ ፤ ዓመፅ ፡ ወይም ፡ ክፉ ፡ በደል ፡ ቢሆን ፡ እን ድታገሣችሁ ፡ በተገባኝ ፤ ፲፭ ስለ ፡ ቃልና ፡ ስለ ፡ ስሞች ፡ ስለ ፡ ሕጋችሁም ፡ የምትከራከሩ ፡ ከሆነ ፡ ግን ፤ ራሳችሁ ፡ ተጠንቀቁ ፤ እኔ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ፈራጅ ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ አልፈቅድምና ፡ አላ ቸው ። ፲፮ ከፍርድ ፡ ወንበርም ፡ ፊት ፡ አስወጣ ቸው ። ፲፯ የግሪክ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ የምኵራብ ፡ አለቃ ፡ ሶስቴንስን ፡ ይዘው ፡ በወንበሩ ፡ ፊት ፡ መቱት ፤ በእነዚህም ፡ ነገሮች ፡ ጋልዮስ ፡ ግድ ፡ የለውም ፡ ነበር ።

፲፰ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ጳውሎስ ፡ እጅግ ፡ ቀን ፡ ተቀ ምጦ ፡ ወንድሞቹንም ፡ ተሰናብቶ ፡ በመርከብ ፡ ወደ ፡ ሶርያ ፡ ሄደ ፤ ስለትም ፡ ነበረበትና ፡ ራሱን ፡ በክንክራኦስ ፡ ተላጨ ፤ ጵርስቅላና ፡ አቂላም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነበሩ ። ፲፱ ወደ ፡ ኤፌሶንም ፡ በደ ረሱ ፡ ጊዜ ፡ እነዚያን ፡ ከዚያ ፡ ተዋቸው ፤ ራሱ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ምኵራብ ፡ ገብቶ ፡ ከአይሁድ ፡ ጋር ፡ ይነጋገር ፡ ነበር ። ፳ እነርሱም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ እን ዲቀመጥላቸው ፡ ሲለምኑት ፡ እሺ ፡ አላለም ፤ ፳፩ ነገር ፡ ግን ፡ ሲሰናበታቸው ፡— የሚመጣውን ፡ በዓል ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ ይገባ ኛል ፤ እግዚአብሔር ፡ ቢፈቅድ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እና ንተ ፡ ደግሞ ፡ እመለሳለሁ ፡ አላቸው ። ከኤፌ ሶንም ፡ በመርከብ ፡ ተነሣ ።

፳፪ ወደ ፡ ቂሣርያም ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፤ ወጥቶ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሰላምታ ፡ ከሰጠ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ አንጾኪያ ፡ ወረደ ። ፳፫ ጥቂት ፡ ቀንም ፡ ቆይቶ ፡ ወጣ ፤ ደቀ ፡ መዛሙርትንም ፡ ሁሉ ፡ እያጸና ፡ በገላትያ ፡ አገርና ፡ በፍርግያ ፡ በተራ ፡ አለፈ ።

፳፬ በመገኑም ፡ የእስክንድርያ ፡ ሰው ፡ የሆነ ፡ ነገር ፡ አዋቂ ፡ የነበረ ፡ አጵሎስ ፡ የሚሉት ፡ አንድ ፡ አይ ሁዳዊ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ኤፌሶን ፡ ወረደ ፤ እርሱም ፡ በመጻሕፍት ፡ እውቀት ፡ የበረታ ፡ ነበረ ። ፳፭ እርሱ ፡ የጌታን ፡ መንገድ ፡ የተማረ ፡ ነበረ ፤ የዮሐን ስንም ፡ ጥምቀት ፡ ብቻ ፡ አውቆ ፡ በመንፈስ ፡ ሲቃጠል ፡ ስለ ፡ ኢየሱስ ፡ ይናገርና ፡ በትክክል ፡ ያስተምር ፡ ነበር ። ፳፮ እርሱም ፡ በምኵራብ ፡ ገልጦ ፡ ይናገር ፡ ጀመር ። ጵርስቅላና ፡ አቂላም ፡ በሰ ሙት ፡ ጊዜ ፤ ወስደው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መን ገድ ፡ ከፊት ፡ ይልቅ ፡ በትክክል ፡ ገለጡለት ። ፳፯ እርሱም ፡ ወደ ፡ አካይያ ፡ ማለፍ ፡ በፈቀደ ፡ ጊዜ ፤ ወንድሞቹ ፡ አጸናኑት ፤ ይቀበሉትም ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ ጻፉለት ፤ በደረሰም ፡ ጊዜ ፡ አምነው ፡ የነበሩትን ፡ በጸጋ ፡ እጅግ ፡ ይጠ ቅማቸው ፡ ነበር ፤ ፳፰ ኢየሱስ ፡ እርሱ ፡ ክርስቶስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከመጻሕፍት ፡ እየገለጠ ፡ ለአይሁድ ፡ በሁሉ ፡ ፊት ፡ በጽኑ ፡ ያስረዳቸው ፡ ነበርና ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ አጵሎስም ፡ በቆሮንቶስ ፡ ሳለ ፡ ጳውሎስ ፡ በላይኛው ፡ አገር ፡ አልፎ ፡ ወደ ፡ ኤፌሶን ፡ መጣ ፤

፲፰ ። ፩ ፤ ምዕ ፲፯ ፥ ፲፭ ፡ ፲፮ ። ፪ ፤ ገሀ ፩ ፥ ፲፫ ፤ ሕዝ ፫ ፥ ፲፰ ፡ ፲፱ ። ፱ ፡ ፲ ፤ ምዕ ፳፫ ፥ ፲፩ ፤ ፳፯ ፥ ፳፫ ፤ ኤር ፩ ፥ ፰ ። ፲፱ ፤ ማቴ ፲ ፥ ፲፰ ። ፲፰ ፤ ምዕ ፳፩ ፥ ፳፬ ፤ ዘኍል ፮ ፥ ፲፰ ።

፪ አንዳንድ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርትንም ፡ አገኘ ። ባመናችሁ ፡ ጊዜ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ተቀበላችሁን ? አላቸው ። እነርሱም ፦ አልተቀበልንም ፤ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ እንዳለ ፡ ስንኳ ፡ አል
፫ ሰማንም ፡ አሉት ። እንኪያ ፡ በምን ፡ ተጠመቃችሁ ? አላቸው ። እነርሱም ፦ በዮሐንስ ፡ ጥም
፬ ቀት ፡ አሉት ። ጳውሎስም ፦ ዮሐንስስ ፡ ከእርሱ ፡ በኋላ ፡ በሚመጣው ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ያምኑ ፡ ዘንድ ፡ ለሕዝብ ፡ እየተናገረ ፡ በን
፭ ስሐ ፡ ጥምቀት ፡ አጠመቀ ፡ አላቸው ። ይህንም ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ ስም ፡ ተጠ
፮ መቁ ፤ ጳውሎስም ፡ እጁን ፡ በጫነባቸው ፡ ጊዜ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ወረደባቸው ፡ በልሳኖችም ፡
፯ ተናገሩ ÷ ትንቢትም ፡ ተናገሩ ። ሰዎቹም ፡ ሁሉ ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ያህሉ ፡ ነበር ።

፰ ወደ ፡ ምኵራብም ፡ ገብቶ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ እየተነጋገረና ፡ እያስረዳቸው ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ ያህል ፡ በግልጥ ፡ ይናገር ፡
፱ ነበር ። አንዳንዶች ፡ ግን ፡ እልከኞች ፡ ሆነው ፡ በሕዝብ ፡ ፊት ፡ መንገዱን ፡ እየሰደቡ ፡ ባላመኑ ፡ ጊዜ ÷ ከእነርሱ ፡ ርቆ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርትን ፡ ለየ ÷ ጢራኖስም ፡ በሚሉት ፡ በትምህርት ፡ ቤት ፡
፲ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ይነጋገር ፡ ነበር ። በእስያም ፡ የኖሩት ፡ ሁሉ ፡ አይሁድም ፡ የግሪክ ፡ ሰዎችም ፡ የጌታን ፡ ቃል ፡ እስኪሰሙ ፡ ድረስ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ያህል ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ።

፲፩ እግዚአብሔርም ፡ በጳውሎስ ፡ እጅ ፡ የሚያስ
፲፪ ገርም ፡ ተአምራት ፡ ያደርግ ፡ ነበር ፤ ስለዚህም ፡ ከአካሉ ፡ ጨርቅ ፡ ወይም ፡ ልብስ ፡ ወደ ፡ ድውዮች ፡ ይወስዱ ፡ ነበር ÷ ደዌያቸውም ፡ ይለቃቸው ፡ ነበር ፡ ክፉዎች ፡ መናፍስትም ፡ ይወጡ ፡
፲፫ ነበር ። አጋንንትንም ፡ እያወጡ ፡ ይዞሩ ፡ ከነበሩት ፡ አይሁድ ፡ አንዳንዶች ፦ ጳውሎስ ፡ በሚሰብከው ፡ በኢየሱስ ፡ እናምላችኋለን ፡ እያሉ ፡ ክፉዎች ፡ መናፍስት ፡ በሉባቸው ፡ ላይ ፡ የጌታን ፡ የኢየሱስን ፡ ስም ፡ ይጠሩባቸው ፡ ዘንድ ፡
፲፬ ሞከሩ ። የካህናትም ፡ አለቃ ፡ ስሆን ፡ አስቄዋ ፡ ለሚሉት ፡ ስአንድ ፡ አይሁዳዊ ፡ ይህን ፡ ያደረጉ ፡
፲፭ ሰባት ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ። ክፉው ፡ መንፈስ ፡ ግን ፡ መልሶ ፦ ኢየሱስንስ ፡ አውቀዋለሁ ፡ ጳውሎስንም ፡ አውቀዋለሁ ፤ እናንተስ ፡ እነማን ፡
፲፮ ናችሁ ? አላቸው ። ክፉው ፡ መንፈስም ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ ዘለለባቸው ፡ ቈስለውም ፡ ከዚያ ፡ ቤት ፡ ዕራቁታቸውን ፡ እስኪሸሹ ፡ ድረስ ፡ በረ
፲፯ ታባቸው ፡ አሸነፋቸውም ። ይህም ፡ በኤፌሶን ፡ በሚኖሩት ፡ ሁሉ ፡ በአይሁድና ፡ በግሪክ ፡ ሰዎች ፡ ዘንድ ፡ የታወቀ ፡ ሆነ ÷ በሁላቸውም ፡ ላይ ፡ ፍርሃት ፡ ወደቀባቸው ፤ የጌታም ፡ የኢየሱስ ፡ ስም ፡
፲፰ ተከበረ ፤ አምነውም ፡ ከነበሩት ፡ እጅግ ፡ ሰዎች ፡ ያደረጉትን ፡ እየተናዘዙና ፡ እየተናገሩ ፡ ይመጡ ፡
፲፱ ነበር ። ከአስማተኞችም ፡ ብዙዎቹ ፡ መጽሐፋቸውን ፡ ሰብስበው ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ አቃ ጠሉት ፤ ዋጋውም ፡ ቢታሰብ ፡ አምሳ ፡ ሺህ ፡
፳ ብር ፡ ሆኖ ፡ ተገኘ ። እንዲህም ፡ የጌታ ፡ ቃል ፡ በኃይል ፡ ያድግና ፡ ያሸንፍ ፡ ነበር ።

፳፩ ይህም ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ ጳውሎስ ፦ ወደ ዚያ ፡ ደርሼ ፡ ሮሜን ፡ ደግሞ ፡ አይ ፡ ዘንድ ፡ ይገባኛል ፡ ብሎ ፡ በመቄዶንያና ፡ በአካይያ ፡ አልፎ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እንዲሄድ ፡ በመንፈስ ፡
፳፪ አሰበ ። ከሚያገለግሉትም ፡ ሁለቱን ፡ ጢሞቴዎስንና ፡ ኤርastosን ፡ ወደ ፡ መቄዶንያ ፡ ልኮ ፡ ራሱ ፡ በእስያ ፡ ጥቂት ፡ ቀን ፡ ቆየ ።

፳፫ በዚያም ፡ ጊዜ ፡ ስለዚህ ፡ መንገድ ፡ ብዙ ፡
፳፬ ሁከት ፡ ሆነ ። ብር ፡ ሠሪ ፡ የሆነ ፡ ድሜጥሮስ ፡ የሚሉት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ የአርጤምስን ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ምስሎች ፡ በብር ፡ እየሠራ ፡ ለአንጥ
፳፭ ረኞች ፡ እጅግ ፡ ትርፍ ፡ ያገኝ ፡ ነበርና ፤ እነዚህንም ፡ ይህንም ፡ የሚመስለውን ፡ ሥራ ፡ የሠሩትን ፡ ሰብስቦ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፦ ሰዎች ፡ ሆይ ÷ ትርፋችን ፡ በዚህ ፡ ሥራ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
፳፮ ታውቃላችሁ ። ይህም ፡ ጳውሎስ ፦ በእጅ ፡ የተሠሩቱ ፡ አማልክት ፡ አይደሉም ፡ ብሎ ÷ በኤፌሶን ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ከጥቂት ፡ ክፍል ፡ በቀር ፡ በእስያ ፡ ሁሉ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብን ፡ እንደ ፡ አስረዳና ፡ እንደ ፡ አሳተ ፡ አይታችኋል ፡ ሰምታችሁማል ።
፳፯ ሥራችንም ፡ እንዲናቅ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ÷ እስያ ፡ ሁሉ ፡ ዓለሙም ፡ የሚያመልከት ፡ የታላቂቱ ፡ አምላክ ፡ የአርጤምስ ፡ መቅደስ ፡ ምናምን ፡ ሆኖ ፡ እንዲቈጠር ፡ እንጂ ÷ ታላቅነትዋም ፡ ደግሞ ፡ እንዳይሻር ፡ ያስፈራል ።

፳፰ ይህንም ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ቍጣ ፡ሞላባቸው ፦ የኤፌሶን ፡ አርጤምስ ፡ ታላቅ ፡ ናት ፡ እያሉም ፡
፳፱ ጮኹ ። ከተማውም ፡ በሙሉው ፡ ተደበለቀ ÷ የመቄዶንያም ፡ ሰዎች ፡ የጳውሎስን ፡ ጓደኞች ፡ ጋይዮስንና ፡ አርስጥሮኮስን ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ነጥቀው ፡ በአንድ ፡ ልብ ፡ ሆነው ፡ ወደ ፡ ጨዋታ ፡
፴ ስፍራ ፡ ሮጡ ። ጳውሎስም ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ ይገባ ፡ ዘንድ ፡ በፈቀደ ፡ ጊዜ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርት ፡
፴፩ ከለከሉት ። ከእስያም ፡ አለቆች ፡ ወዳጆቹ ፡ የሆኑት ፡ አንዳንዶች ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ልከው ፡ ወደ ፡ ጨዋታ ፡ ስፍራ ፡ ራሱን ፡ እንዳይሰጥ ፡
፴፪ ለመኑት ። ወዲያና ፡ ወዲህም ፡ እያሉ ፡ ይጮኹ ፡ ነበር ፤ ጉባኤው ፡ ድብልቅልቅ ፡ ሆኖ ፡ የሚበልጡት ፡ ስንኳ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ተሰበሰቡ ፡
፴፫ አላወቁም ፡ ነበርና ። አይሁድም ፡ ሲያቀርቡት ÷ እስክንድሮስን ፡ ከሕዝቡ ፡ መካከል ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ገፉት ፤ እስክንድሮስም ፡ በእጁ ፡ ጠቅሶ ፡ በሕ
፴፬ ዝብ ፡ ፊት ፡ እንዲምዋገትላቸው ፡ ወደደ ። አይሁዳዊ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በወቁ ፡ ጊዜ ÷ ሁሉ ፡ በአንድ ፡ ድምፅ ፦ የኤፌሶን ፡ አርጤምስ ፡ ታላቅ ፡ ናት ፡ እያሉ ፡ ሁለት ፡ ሰዓት ፡ ያህል ፡
፴፭ ጮኹ ። የከተማይቱም ፡ ጸሐፊ ፡ ሕዝቡን ፡ ጸጥ ፡ አሰኝቶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ የኤፌሶን ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ÷ የኤፌሶን ፡ ከተማ ፡ ለታላቂቱ ፡ አርጤ

፲፱። ፪፤ ምዕ· ፲፰ ÷ ፳፬ ፣ ፳፭ ። ፬፤ ማቴ· ፫ ÷ ፲፩ ። ፭፤ ምዕ· ፰ ÷ ፲፮ ። ፮፤ ምዕ· ፰ ÷ ፲፯ ፤ ፲ ÷ ፵፮ ። ፲፱፤ ምዕ· ፳ ÷ ፲፮ ።
፳፩፤ ማቴ· ፳ ÷ ፳፱ ፣ ፳፫ ። ፳፱፤ ሮሜ· ፲፮ ÷ ፳፫ ፤ ፪ ጢሞ· ፬ ÷ ፳ ።

ምስ ፡ ከሰማይም ፡ ስወረደው ፡ ጣዖትዋ ፡ የመቅደስ ፡ ጠባቂ ፡ መሆንዋን ፡ የማያውቅ ፡ ሰው ፡ ፴፮ ማን ፡ ነው ? ይህንም ፡ የሚከደው ፡ ከሌለ ÷ ጸጥ ፡ እንድትሉና ፡ አንዳች ፡ በችኩላ ፡ እንዳታ ፴፯ ደርጉ ፡ ይገባል ። የመቅደስን ፡ ዕቃ ፡ ያልሰረቁ ፡ አምላስችንንም ፡ ያልሰደቡ ፡ እነዚህን ፡ ሰዎች ፡ ፴፰ አምጥታችኋቸዋልና ። ድሜጥሮስና ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ያሉት ፡ እንጥረኞች ፡ ግን ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ነገር ፡ እንዳላቸው ÷ የመጋቢያ ፡ ቀንና ፡ አገረ ፡ ገዢዎች ፡ አሉ ፤ እርስ ፡ በርስቸው ፡ ይምዋገቱ ። ፴፱ ስለ ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ እንዳች ፡ ብትፈልጉ ÷ በተደነገገው ፡ ጉባኤ ፡ ይፈታል ። ፵ ዛሬ ፡ ስለ ፡ ተደረገው ፡— ሁከት ፡ ነው ፡ ሲሉ ፡ እንዳይከሱን ፡ ያስፈራልና ፤ ስለዚህም ፡ ስብሰብ ፡ ምላሽ ፡ መስጠት ፡ አንችልም ÷ ምክንያት ፡ የለ ፵፩ ምና ። ይህንም ፡ ብሎ ፡ ጉባኤውን ፡ ፈታው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ ሁከቱም ፡ ከቀረ ፡ በኋላ ፡ ጳውሎስ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ አስመጥቶ ፡ መከራቸው ÷ ተሰናብቶ አቸውም ፡ ወደ ፡ መቄዶንያ ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ ፪ ወጣ ። ያንም ፡ አገር ፡ እያለፈ ፡ በብዙ ፡ ቃል ፡ ከመከራቸው ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ግሪክ ፡ አገር ፡ መጣ ። ፫ በዚያም ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ ተቀምጦ ፡ ወደ ፡ ሶርያ ፡ በመርከብ ፡ ሊሄድ ፡ ባሰበ ፡ ጊዜ ፡ አይሁድ ፡ ሴራ ፡ ስላደረጉበት ፡ በመቄዶንያ ፡ አልፎ ፡ ይመ ፬ ለስ ፡ ዘንድ ፡ ቈረጠ ። የሸኙትም ፡ የቤርያው ፡ ሱሲጳጥሮስ ፡ ከተሰሎንቄ ፡ ሰዎችም ፡ አርስጥሮኮስና ፡ ሲኮንዱስ ፡ የደርቤኑም ፡ ጋይዮስና ፡ ጢሞቴዎስ ፡ የእስያ ፡ ሰዎችም ፡ ቲኪቆስ ፡ ጥሮፊሞ ፭ ስም ፡ ነበሩ ፤ እነዚህም ፡ ወደ ፡ ፊታችን ፡ አል ፮ ፈው ፡ በጢሮአዳ ፡ ቆዩን ። እኛ ፡ ግን ፡ ከቂጣ ፡ በዓል ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ከፊልጵስዩስ ፡ በመርከብ ፡ ተነሥተን ፡ በአምስት ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ጢሮአዳ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ደረስንና ፡ በዚያ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ተቀመጥን ።

፯ ከሰምንቱም ፡ በመጀመሪያ ፡ ቀን ፡ እንጀራ ፡ ለመቍረስ ፡ ተሰብስበን ፡ ሳለን ÷ ጳውሎስ ፡ በነገው ፡ ሊሄድ ፡ ስላሰበ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ይነጋገር ፡ ነበር ÷ እስከ ፡ መንፈቀ ፡ ሌሊትም ፡ ነገሩን ፡ ፰ አስረዘመ ። ተሰብስበንም ፡ በነበርንበት ፡ ሰገ ፱ ነት ፡ እጅግ ፡ መብራት ፡ ነበረ ። አውጤኪስ ፡ የሚሉትም ፡ አንድ ፡ ጎበዝ ፡ በመስኮት ፡ ተቀምጦ ፡ ታላቅ ፡ እንቅልፍ ፡ አንቀላፍቶ ፡ ነበር ፡ ጳውሎስም ፡ ነገርን ፡ በስረዘመ ፡ ጊዜ ፡ እንቅልፍ ፡ ከብዶት ፡ ከሦስተኛው ፡ ደርብ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ ፲ ወደቀ ÷ ሞቶም ፡ አነሡት ። ጳውሎስም ፡ ወርዶ ፡ በላዩ ፡ ወደቀ ÷ አቅፎም ፡— ነፍሱ ፡ አለችበትና ፡ ፲፩ አትንጫጩ ፡ አላቸው ። ወጥቶም ፡ እንጀራ ፡ ቈርሶም ፡ በላ ፤ ብዙ ፡ ጊዜም ፡ እስኪነጋ ፡ ድረስ ፡ ፲፪ ተነጋገረ ፡ እንዲህም ፡ ሄደ ። ብላቴናውንም ፡ ደኅና ፡ ሆኖ ፡ ወሰዱት ፡ እጅግም ፡ ተጽናኑ ።

፲፫ እኛ ፡ ግን ፡ ጳውሎስን ፡ ከዚያ ፡ እንቀበለው ፡ ዘንድ ፡ ስላስን ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ቀድመን ፡ ሄድ ንና ፡ ወደ ፡ አሶን ፡ ተነሣን ፤ እርሱ ፡ በመሬት ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ ስላሰበ ፡ እንደዚህ ፡ አዞ ፡ ነበርና ። ፲፬ በአሶንም ፡ ባገኘን ፡ ጊዜ ፡ ተቀብለነው ፡ ወደ ፡ ፲፭ ሚጢሊኒ ፡ መጣን ፤ በማግሥቱም ፡ ከዚያ ፡ በባሕር ፡ ተነሥተን ፡ በኪዩ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ደረስን ÷ በነገውም ፡ ወደ ፡ ሳሞን ፡ ተሻገርን ፤ በትሮጊሊዮም ፡ አድረን ፡ በማግሥቱ ፡ ወደ ፡ ሚሊጢን ፡ ፲፮ መጣን ። ጳውሎስ ፡ በእስያ ፡ እጅግ ፡ እንዳይቀመጥ ፡ ኤፌሶንን ፡ ይተው ፡ ዘንድ ፡ ቈርጦ ፡ ነበርና ፤ ቢቻለውም ፡ በዓለ ፡ ኀምሳን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ይውል ፡ ዘንድ ፡ ይቸኵል ፡ ነበርና ።

፲፯ ከሚሊጢንም ፡ ወደ ፡ ኤፌሶን ፡ልኮ ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ሽማግሌዎች ፡ አስጠራቸው ፤ ፲፰፡፲፱ ወደ ፡ እርሱም ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡—

ወደ ፡ እስያ ፡ ከገባሁበት ፡ ከመጀመሪያ ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ÷ በትሕትና ፡ ሁሉና ፡ በእንባ ፡ ከአይሁድም ፡ ሴራ ፡ በደረሰብኝ ፡ ፈተና ፡ ስጌታ ፡ አየተገዛሁ ፡ ዘመኑን ፡ ሁሉ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ኖርሁ ፡ እናንተው ፡ ታውቃላችሁ ፤ ፳፡፳፩ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ንስሐንና ፡ በጌታችን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ማመንን ፡ ስአይሁድና ፡ ስግሪክ ፡ ሰዎች ፡ እየመሰከርሁ ፡ በጉባኤም ፡ በየቤታችሁም ፡ እወራሁላችሁና ፡ አስተማርኋችሁ ፡ እንጂ ÷ ከሚጠቅማችሁ ፡ ነገር ፡ አንዳች ፡ ፳፪ ስንኳ ፡ አላስቀረሁባችሁም ። አሁንም ÷ እነሆ ÷ እኔ ፡ በመንፈስ ፡ ታስሬ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እሄዳለሁ ÷ በዚያም ፡ የሚያገኘኝ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፳፫ አላውቅም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡— እስራትና ፡ መከራ ፡ ይቆይሃል ፡ ብሎ ፡ በየከተ ፳፬ ማው ፡ ሁሉ ፡ ይመሰክርልኛል ። ነገር ፡ ግን ፡ ሩጫዬንና ፡ ከጌታ ፡ ከኢየሱስ ፡ የተቀበልሁትን ፡ አገልግሎት ፡ እርሱም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ጸጋ ፡ ወንጌልን ፡ መመስከር ፡ እፈጽም ፡ ዘንድ ፡ ነፍሴን ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ እንደማትከብር ፡ እንደ ፡ ከንቱ ፡ ፳፭ ነገር ፡ እቈጥራለሁ ። አሁንም ÷ እነሆ ÷ እኔ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ እየሰበክሁ ፡ በመካከላችሁ ፡ የዞርሁ ፡ ሁላችሁ ፡ ከእንግዲህ ፡ ፳፮ ወዲህ ፡ ፊቴን ፡ እንዳታዩ ፡ አውቃለሁ ። ስለ ዚህ ፡ እኔ ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ደም ፡ ንጹሕ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ ዛሬ ፡ በዚች ፡ ቀን ፡ እመሰክርላችኋለሁ ። ፳፯ የእግዚአብሔርን ፡ ምክር ፡ ሁሉ ፡ ነግሬአችኋለ ፳፰ ሁና ÷ ምንም ፡ አላስቀረሁባችሁም ። በገዛ ፡ ደሙ ፡ የዋጃትን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ትጠብቁአት ፡ ዘንድ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ እናንተን ፡ ጳጳሳት ፡ አድርጎ ፡ ስሾመበት ፡ ስመንጋው ፡ ሁሉና ፡ ስራሳችሁ ፡ ተጠንቀቁ ። ከሄ ፳፱፡፴ ድሁ ፡ በኋላ ፡ ስመንጋው ፡ የማይራሩ ፡ ጨካኞች ፡ ተኩላዎች ፡ እንዲገቡባችሁ ÷ ደቀ ፡ መዛሙርትንም ፡ ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ይስቡ ፡ ዘንድ ፡ ጠማማ ፡

፳። ፬ ፤ ም. ፲፱ ÷ ፳፱ ። ፯ ፤ ም. ፪ ÷ ፵፪ ፡ ፵፮ ። ፲ ፤ ፩ ነገሥ. ፲፯ ÷ ፳፩ ። ፲፯ ፤ ም. ፬ ÷ ፭ ። ፳፫ ፤ ም. ፳፩ ÷ ፳፬ ። ፳፬ ፤ ማቴ. ፮ ÷ ፲፭ ። ፴ ፤ ሉቃ. ፪ ÷ ፪ ።

ነገርን ፡ የሚናገሩ ፡ ሰዎች ፡ በመካከላችሁ ፡ እን
፴፩ ዲነሡ ፡ እኔ ፡ አውቃለሁ ። ስለዚህ ፡ ሦስት ፡
ዓመት ፡ ሌሊትና ፡ ቀን ፡ በእንባ ፡ እያንዳንዳች
ሁን ፡ ከመገሠጽ ፡ እንዳላቋረጥሁ ፡ እያሰባችሁ ፡
፴፪ ትጉ ። አሁንም ፡ በእግዚአብሔርና ፡ ያንጻችሁ ፡
ዘንድ ፡ በቅዱሳንም ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ ርስትን ፡
ይሰጣችሁ ፡ ዘንድ ፡ ለሚችል ፡ ለጸጋው ፡ ቃል ፡
፴፫ አደራ ፡ ሰጥቻችኋለሁ ። ከማንም ፡ ብር ፡ ወይም ፡
፴፬ ወርቅ ፡ ወይም ፡ ልብስ ፡ አልተመኘሁም ፤ እነ
ዚህ ፡ እጆቼ ፡ በሚያስፈልገኝ ፡ ነገር ፡ ለእኔና ፡
ከእኔ ፡ ጋር ፡ ላሉት ፡ እንዳገለገሉ ፡ እናንተ ፡ ታው
፴፭ ቃላችሁ ። እንዲሁ ፡ እየደከማችሁ ፡ ድውዮ
ችን ፡ ልትረዱና ፡ እርሱ ፡ ራሱ ፡— ከሚቀበል ፡
ይልቅ ፡ የሚሰጥ ፡ ብፁዕ ፡ ነው ፡ እንዳለ ፡ የጌ
ታን ፡ የኢየሱስን ፡ ቃል ፡ ልታስቡ ፡ ይገባችሁ ፡
ዘንድ ፡ በሁሉ ፡ አሳየኋችሁ ።

፴፮ ይህንም ፡ ብሎ ፡ ተንበርክኮ ፡ ከሁላቸው ፡
፴፯ ጋር ፡ ጸለየ ። ሁሉም ፡ እጅግ ፡ አለቀሱ ፥ ጳው
ሎስንም ፡ አንገቱን ፡ አቅፈው ፡ ይስሙት ፡ ነበር ፤
፴፰ ይልቁንም ፡— ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ፊቴን ፡ አታ
ዩም ፡ ስላላቸው ፡ ነገር ፡ እጅግ ፡ አዘኑ ። እስከ ፡
መርከብም ፡ ድረስ ፡ሸኙት ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ ከእነርሱም ፡ ተለይተን ፡ ተነሣን ፤ በቀጥታም ፡
ሄደን ፡ ወደ ፡ ቆስ ፡ በነገውም ፡ ወደ ፡ ሩድ ፡ ከዚ
፪ ያም ፡ ወደ ፡ ጳጥራ ፡ መጣን ፤ ወደ ፡ ፊንቄም ፡ የሚ
ሻገር ፡ መርከብ ፡ አግኝተን ፡ ገባንና ፡ ተነሣን ።
፫ ቆጵሮስንም ፡ ባየናት ፡ ጊዜ ፡ በስተ ፡ግራችን ፡
ተውናት ፡ ወደ ፡ ሶርያም ፡ ሄደን ፡ ወደ ፡ ጢሮስ ፡
ደረስን ፥ መርከቡ ፡ ሸክሙን ፡ በዚያ ፡ የሚያ
፬ ራግፍ ፡ ነበርና ። ደቀ ፡ መዛሙርትንም ፡ ባገ
ኘን ፡ ጊዜ ፡ በዚያ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ተቀመጥን ፤
እነርሱም ፡ ጳውሎስን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እን
፭ ዳይወጣ ፡ በመንፈስ ፡ አሉት ። ጊዜውንም ፡ በፈ
ጸምን ፡ ጊዜ ፡ ወጥተን ፡ ሄድን ፤ ሁላቸውም ፡ ከሚ
ስቶቻቸውና ፡ ከልጆቻቸው ፡ ጋር ፡ እስከ ፡ ከተ
ማው ፡ ውጭ ፡ ድረስ ፡ ሸኙን ፥ በባሕሩም ፡ ዳር ፡
፮ ተንበርክከን ፡ጸለይን ፤ እርስ ፡ በርሳችንም ፡
ተሰነባብተን ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ ወጣን ፥ እነዚያም ፡
ወደ ፡ ቤታቸው ፡ ተመለሱ ።

፯ እኛም ፡ የባሕሩን ፡ መንገድ ፡ ፈጽመን ፡ ከጢ
ሮስ ፡ ወደ ፡ አካ ፡ ደረስን ፤ ለወንድሞችም ፡ ሰላ
ምታ ፡ ሰጥተን ፡ ከእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡
፰ ተቀመጥን ። በነገውም ፡ ወጥተን ፡ ወደ ፡ ቂሣ
ርያ ፡ መጣን ፥ ከሰባቱም ፡ አንድ ፡ በሚሆን ፡ በወ
ንጌላዊው ፡ ፊልጶስ ፡ ቤት ፡ ገብተን ፡ በእርሱ ፡
፱ ዘንድ ፡ ተቀመጥን ። ለእርሱም ፡ ትንቢት ፡ የሚ
ናገሩ ፡ አራት ፡ ደናግል ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ነበ
፲ ሩት ። አያሌ ፡ ቀንም ፡ ተቀምጠን ፡ ሳለን ፡ ነቢይ ፡
የነበረ ፡ አጋቦስ ፡ የሚሉት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ከይ
ሁዳ ፡ ወረደ ። ወደ ፡ እኛም ፡ መጣና ፡ የጳውሎ ፲፩
ስን ፡ መታጠቂያ ፡ ወስዶ ፡ የገዛ ፡ እጁንና ፡ እግ
ሩን ፡ አስሮ ፡— እንዲሁ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡—
ይህ ፡ መታጠቂያ ፡ ያለውን ፡ ሰው ፡ አይሁድ ፡ በኢ
የሩሳሌም ፡ እንደዚህ ፡ ያስሩታል ፡ በአሕዛብም ፡
እጅ ፡ አሳልፈው ፡ ይሰጡታል ፡ ይላል ፡ አለ ።
፲፪ ይህንም ፡ በሰማን ፡ ጊዜ ፡ እኛም ፡ በዚያ ፡ የሚ
ኖሩትም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እንዳይወጣ ፡ ለመ
፲፫ ንነው ። ጳውሎስ ፡ ግን ፡ መልሶ ፡— እያለቀሳ
ችሁ ፡ ልቤንም ፡ እየሰበራችሁ ፡ ምን ፡ ማድረጋ
ችሁ ፡ ነው ? እኔ ፡ ስለ ፡ ጌታ ፡ ስለ ፡ ኢየሱስ ፡ ስም ፡
በኢየሩሳሌም ፡ ለመሞት ፡ እንኳ ፡ ተሰናድቼአ
ለሁ ፡ እንጂ ፡ ለእስራት ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ አለ ።
፲፬ ምክርንም ፡ ሊቀበል ፡ እምቢ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡—
የጌታ ፡ ፈቃድ ፡ ይሁን ፡ ብለን ፡ዝም ፡ አልን ።
፲፭ ከዚህም ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ተዘጋጅተን ፡ ወደ ፡
፲፮ ኢየሩሳሌም ፡ ወጣን ። በቂሣርያም ፡ ከነበሩ ፡
ደቀ ፡ መዛሙርት ፡ አንዳንዶች ፡ ደግሞ ፡ ከእኛ ፡
ጋር ፡ መጡ ፥ እነርሱም ፡ ወደምናድርበት ፡ ወደ ፡
ቀደመው ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ወደ ፡ ቆጵሮሱ ፡
ምናሶን ፡ ወደሚሉት ፡ ቤት ፡ መሩን ።
፲፯ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በደረስን ፡ ጊዜ ፡ ወንድ
፲፰ ሞች ፡ በደስታ ፡ ተቀበሉን ። በነገውም ፡ ጳው
ሎስ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ያዕቆብ ፡ ዘንድ ፡ ገባ ፡
፲፱ ሽማግሌዎችም ፡ ሁሉ ፡ መጡ ። ሰላምታም ፡ ከተቀ
ረበላቸው ፡ በኋላ ፡ በእርሱ ፡ ማገልገል ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ያደረገውን ፡ በእ
፳ ያንዳንዱ ፡ ተረከላቸው ። እነርሱም ፡ በሰሙ ፡
ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰገኑ ፡ አሉትም ፡—
ወንድም ፡ ሆይ ፥ በአይሁድ ፡ መካከል ፡ አምነው ፡
የነበሩት ፡ ስንት ፡ አእላፋት ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ታያ
ለህ ፤ ሁላቸውም ፡ ለሕግ ፡ የሚቀኑ ፡ ናቸው ።
፳፩ ልጆቻቸውንም ፡ እንዳይገርዙ ፡ በሥርዓትም ፡
እንዳይሄዱ ፡ ብለህ ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ያሉት ፡
አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ ሙሴን ፡ ይክዱ ፡ ዘንድ ፡ እንድ
፳፪ ታስተምር ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ ነግረዋቸዋል ። እንግ
ዲህ ፡ ምን ፡ ይሁን ? የአንተን ፡ መምጣት ፡ ይሰማ
ሉና ፡ ብዙዎች ፡ የግድ ፡ ሳይሰበሰቡ ፡ አይቀሩም ።
፳፫ እንግዲህ ፡ ይህን ፡ የምንልህን ፡ አድርግ ፤ ስለት ፡
ያለባቸው ፡ አራት ፡ ሰዎች ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ አሉ ።
፳፬ እነዚህንም ፡ ይዘህ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ንጻ ፥ ራሳ
ቸውንም ፡ እንዲላጩ ፡ገንዘብ ፡ ክፈልላቸው ፤
ሁሉም ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ የተማሩት ፡ ከንቱ ፡ እንደ ፡
ሆነና ፡ አንተ ፡ ራስህ ፡ ደግሞ ፡ ሕጉን ፡ እየጠበ
ቅህ ፡ በሥርዓት ፡ እንድትመላለስ ፡ ያውቃሉ ።
፳፭ አምነው ፡ ስለ ፡ ነበሩ ፡ አሕዛብ ፡ ግን ፡ ለጣዖት ፡
ከተሠዋ ፡ ከደምም ፡ ከታነቀም ፡ ከዝሙትም ፡
ነፍሳቸውን ፡ እንዲጠብቁ ፡ ፈርደን ፡ እኛ ፡ጽፈ
፳፮ ንላቸዋል ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ጳውሎስ ፡ ሰዎችን ፡
ይዞ ፡ በማግሥቱ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ እየነጻ ፥ መንጻ
ታቸውን ፡ የሚፈጽሙበትን ፡ ቀን ፡ አስታውቆ ፡

፳ ። ፴፬ ፡ ም. ፲፰ ፥ ፫ ።
፳፩ ። ፱ ፡ ም. ፰ ፥ ፳፫ ። ፰ ፡ ም. ፮ ፥ ፭ ፤ ፰ ፥ ፭ ፡ ፳፮ ፡ ፵ ። ፲ ፡ ም. ፲፩ ፥ ፳፰ ። ፲፩ ፡ ሥ. ፬ ። ፳፬ ፡ ም. ፲፰ ፥ ፲፰ ።
፳፭ ፡ ም. ፲፭ ፥ ፳ ። ፳፮ ፡ ዘኍል. ፮ ፥ ፲፫—፲፰ ።

ወደ ፡ መቅደስ ፡ ገባ ። በዚያም ፡ ቀን ፡ ስለ ፡ እያ
ንዳንዳቸው ፡ መሥዋዕትን ፡ አቀረቡ ።

፳፯፡፳፰ ሰባቱ ፡ ቀንም ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ ሲቀርብ ፡
ከእስያ ፡ የመጡ ፡ አይሁድ ፡ በመቅደስ ፡ አይተ
ውት ፡ ሕዝብን ፡ ሁሉ ፡ አወኩና ፡— የእስራኤል ፡
ሰዎች ፡ ሆይ ፡ እርዱን ፡ ሕዝብን ፡ ሕግንም ፡ ይህ
ንም ፡ ስፍራ ፡ ሲቃወም ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ በየስ
ፍራው ፡ የሚያስተምረው ፡ ሰው ፡ ይህ ፡ ነው ፤
ደግሞም ፡ የግሪክን ፡ ሰዎች ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡
መቅደስ ፡ አግብቶ ፡ ይህን ፡ የተቀደሰ ፡ ስፍራ ፡
አርክሶአል ፡ ብለው ፡ እየጮኹ ፡ እጃቸውን ፡
፳፱ ጫኑበት ። በፊት ፡ የኤፌሶኑን ፡ ጥሮፊሞስን ፡
ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በከተማ ፡ አይተውት ፡ ነበርና ፡
ጳውሎስም ፡ ወደ ፡ መቅደስ ፡ ያገባው ፡ መሰሎ
፴ አቸው ፡ ነው ። ከተማውም ፡ ሁሉ ፡ ታወከ ፡
ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ተሰበሰቡ ፤ ጳውሎስንም ፡
ይዘው ፡ ከመቅደስ ፡ ውጭ ፡ ጐተቱት ፤ ወዲያ
፴፩ ውም ፡ ደጆች ፡ ተዘጉ ። ሊገድሉትም ፡ ሲፈ
ልጉ ፡— ኢየሩሳሌም ፡ ፈጽማ ፡ ታወከች ፡ የሚል ፡
፴፪ ወሬ ፡ ወደ ፡ ጭፍራው ፡ ሻለቃ ፡ ወጣ ፤ እርሱም ፡
ያን ፡ ጊዜ ፡ ወታደሮችን ፡ ከመቶ ፡ አለቆች ፡
ጋር ፡ ይዞ ፡ እየሮጠ ፡ ወረደባቸው ፤ እነርሱም ፡
የሻለቃውንና ፡ ወታደሮችን ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ጳው
፴፫ ሎስን ፡ መምታት ፡ ተዉ ። በዚያን ፡ ጊዜም ፡
የሻለቃው ፡ ቀርቦ ፡ ያዘውና ፡ በሁለት ፡ ሰንሰለት ፡
ይታሰር ፡ ዘንድ ፡ አዘ ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆነና ፡ ምን ፡
፴፬ እንዳደረገ ፡ ጠየቀ ። ሕዝቡም ፡ እኩሌቶቹ ፡
እንዲህ ፡ እኩሌቶቹም ፡ እንዲያ ፡ እያሉ ፡ ይጮኹ ፡
ነበር ፤ ስለ ፡ ጫጫታውም ፡ እርግጡን ፡ ማወቅ ፡
ባልተቻለ ፡ ጊዜ ፤ ወደ ፡ ወታደሮች ፡ ሰፈር ፡ ይወ
፴፭ ስዱት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ። ወደ ፡ ደረጃውም ፡ በደ
ረሰ ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ ሕዝቡ ፡ ግፊያ ፡ ወታደሮች ፡
፴፮ እንዲሸከሙት ፡ ሆነ ፤ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡— አስወ
ግደው ፡ እያሉና ፡ እየጮኹ ፡ ይከተሉ ፡ ነበርና ።

፴፯ ወደ ፡ ሰፈርም ፡ ሊያገቡት ፡ በቀረቡ ፡ ጊዜ ፤
ጳውሎስ ፡ የሻለቃውን ፡— አንድ ፡ ነገር ፡ ብነግ
ርህ ፡ ትፈቅድልህን ? አለው ። እርሱም ፡— የግ
፴፰ ሪክ ፡ ቋንቋ ፡ ታውቃለህን ? አንተ ፡ ከዚህ ፡
ዘመን ፡ አስቀድሞ ፡ ከነፍሰ ፡ ገዳዮቹ ፡ አራቱን
ሺህ ፡ ሰዎች ፡ አሸፍተህ ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
ያወጣህ ፡ የግብፅ ፡ ሰው ፡ አይደለህምን ? አለ ።
፴፱ ጳውሎስ ፡ ግን ፡— እኔስ ፡ አይሁዳዊ ፡ በኪልቅያ ፡
ያለው ፡ የጠርሴስ ፡ ሰው ፡ ሆኜ ፡ ስመ ፡ ጥር ፡
በሆነ ፡ ከተማ ፡ የምኖር ፡ ነኝ ፤ ለሕዝቡ ፡ እናገር ፡
ዘንድ ፡ እንድትፈቅድልኝ ፡ እለምንሃለሁ ፡ አለ ።
፵ በፈቀደለትም ፡ ጊዜ ፡ ጳውሎስ ፡ በደረጃው ፡
ላይ ፡ ቆሞ ፡ በእጁ ፡ ወደ ፡ ሕዝቡ ፡ ጠቀሰ ፡ እጅ
ግም ፡ ጸጥታ ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ በዕብራይስጥ ፡ ቋንቋ ፡
እየተናገረ ፡ እንዲህ ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩ እናንተ ፡ ወንድሞች ፡ አባቶችም ፤ አሁን ፡ ስእ
ናንተ ፡ ነገሬን ፡ ስገልጥ ፡ ስሙኝ ።

፪ በዕብራይስጥም ፡ ቋንቋ ፡ ሲናገር ፡ በሰሙ ፡
ጊዜ ፡ ከፊት ፡ ይልቅ ፡ ገዝም ፡ አሉ ። እርሱም ፡
አለ ፡—

፫ እኔ ፡ የኪልቅያ ፡ በምትሆን ፡ በጠርሴስ ፡ የተወ
ለድሁ ፤ በዚችም ፡ ከተማ ፡ በገማልያል ፡ እግር ፡
አጠገብ ፡ ያደግሁ ፡ የአባቶችንም ፡ ሕግ ፡ ጠን
ቅቄ ፡ የተማርሁ ፤ ዛሬውንም ፡ እናንተ ፡ ሁሉ ፡
እንድትሆኑ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቀናተኛ ፡ የሆንሁ ፡
፬ አይሁዳዊ ፡ ሰው ፡ ነኝ ። ወንዶችንም ፡ ሴቶች
ንም ፡ እያሰርሁ ፡ ወደ ፡ ወኅኒም ፡ እሳልፌ ፡ እየሰ
ጠሁ ፡ ይህን ፡ መንገድ ፡ እስከ ፡ ሞት ፡ ድረስ ፡ አሳ
፭ ደድሁ ። እንዲሁም ፡ ሊቀ ፡ ካህናቱ ፡ ደግሞ ፡
ሽማግሌዎቹም ፡ ሁሉ ፡ ይመሰክሩልኛል ፤ ከእነ
ርሱ ፡ ደግሞ ፡ መልእክትን ፡ ለወንድሞቻቸው ፡
ተቀብዬ ፤ በደማስቆ ፡ ያሉትን ፡ ደግሞ ፡ ታስ
ረው ፡ እንዲቀጡ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ላመጣ ፡
ወደዚያ ፡ እሄድ ፡ ነበር ።

፮ ስሄድም ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ በቀረብሁ ፡ ጊዜ ፤
ቀትር ፡ ሲሆን ፡ ድንገት ፡ ከሰማይ ፡ ታላቅ ፡ ብር
፯ ሃን ፡ በዙሪያዬ ፡ አንጸባረቀ ፤ በምድርም ፡ ላይ ፡
ወድቄ ፡— ሳውል ፡ ሳውል ፤ ስለ ፡ ምን ፡ ታሳድደ
፰ ኛለህ ? የሚለኝን ፡ ድምፅ ፡ ሰማሁ ። እኔም ፡
መልሼ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፤ አንተ ፡ ማን ፡ ነህ ?
አልሁ ። እርሱም ፡— አንተ ፡ የምታሳድደኝ ፡
፱ የናዝሬቱ ፡ ኢየሱስ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ አለኝ ። ከእኔ ፡
ጋር ፡ የነበሩትም ፡ ብርሃኑን ፡ አይተው ፡ ፈሩ ፤
የሚናገረኝን ፡ የእርሱን ፡ ድምፅ ፡ ግን ፡ አልሰ
፲ ሙም ። ጌታ ፡ ሆይ ፤ ምን ፡ ላድርግ ? አልሁት ።
ጌታም ፡— ተነሥተህ ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ ሂድና ፡
ታደርገው ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ታዘዘው ፡ ሁሉን ፡
፲፩ በዚያ ፡ ይነግሩሃል ፡ አለኝ ። ከዚያ ፡ ብርሃንም ፡
ክብር ፡ የተነሣ ፡ ማየት ፡ ባይሆንልኝ ፡ ከእኔ ፡
ጋር ፡ የነበሩት ፡ ሰዎች ፡ እጄን ፡ ይዘው ፡ እየመ
ሩኝ ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ ደረስሁ ።

፲፪ በዚያም ፡ የኖሩት ፡ አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ የመሰክሩ
ለት ፡ እንደ ፡ ሕጉም ፡ በጸሎት ፡ የተጋ ፡ ሐናንያ ፡
፲፫ የሚሉት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበረ ። እርሱም ፡ ወደ ፡
እኔ ፡ መጥቶ ፡ በአጠገቤም ፡ ቆሞ ፡— ወንድሜ ፡
ሳውል ፡ ሆይ ፤ እይ ፡ አለኝ ። እኔም ፡ ያን ፡ ጊዜ
፲፬ ውን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አየሁ ። እርሱም ፡ አለኝ ፡—
የአባቶቻችን ፡ አምላክ ፡ ፈቃዱን ፡ ታውቅ ፡
ዘንድና ፡ ጻድቁን ፡ ታይ ፡ ዘንድ ፡ ከአፉም ፡ ድም
ፅን ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡ አስቀድሞ ፡ መርጦሃል ፡
፲፭ ባየኸውና ፡ በሰማኸው ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡
፲፮ ምስክር ፡ ትሆንለታለህና ። አሁንስ ፡ ለምን ፡
ትዘገያለህ ? ተነሣና ፡ ስሙን ፡ እየጠራህ ፡ ተጠ
መቅ ፡ ከኃጢአትህም ፡ ታጠብ ።

፲፯ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ከተመለስሁ ፡ በኋላ ፡
፲፰ በመቅደስ ፡ ስጸልይ ፡ ተመስጦ ፡ መጣብኝ ፡ እር
ሱም ፡— ፍጠን ፡ ከኢየሩሳሌምም ፡ ቶሎ ፡
ውጣ ፤ ስለ ፡ እኔ ፡ የምትመሰክረውን ፡ አይቀበ

፳፩ ። ፳፰ ፤ ሕዝ. ፵፬ ፥ ፯ ። ፳፱ ፤ ም. ፳ ፥ ፬ ። ፴፫ ፤ ቍ. ፲ ።
፳፪ ። ፫ ፤ ም. ፳ ፥ ፴፱ ። ፬ ፤ ም. ፰ ፥ ፫ ፣ ፲ ። ፭—፲፮ ፤ ም. ፱ ፥ ፩—፲፰ ፤ ፳፮ ፥ ፲—፲፰ ።

፲፱ ሉህም ፡ ሲለኝ ፡ አየሁት ። እኔም ፡— ጌታ ፡
ሆይ ፥ በአንተ የሚያምኑትን ፡ በምኵራብ ፡
ሁሉ ፡ እኔ ፡ በወኅኒ ፡ አገባና ፡ እደበድብ ፡ እንደ ፡
፳ ነበርሁ ፡ እነርሱ ፡ ያውቃሉ ፤ የሰማዕትህንም ፡
የእስጢፋኖስን ፡ ደም ፡ ባፈሰሱ ፡ ጊዜ ፥ ራሴ ፡
ደግሞ ፡ በአጠገባቸው ፡ ሰቆም ፡ ተስማምቼ ፡
የገዳዮችን ፡ ልብስ ፡ እጠብቅ ፡ ነበር ፡ አልሁ ።
፳፩ እርሱም ፡— ሂድ ፡ እኔ ፡ ወደ ፡ አሕዛብ ፡ ከዚህ ፡
ወደ ፡ሩቅ ፡ እልክሃለሁና ፡ አለኝ ።
፳፪ እስከዚህም ፡ ቃል ፡ድረስ ፡ ይሰሙት ፡ነበር ፥
ድምፃቸውንም ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡— እንደዚህ ፡
ያለውን ፡ ሰው ፡ ከምድር ፡ አስወግደው ፤ በሕይ
ወት ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ አይገባውምና ፡ አሉ ።
፳፫ ሲጮኹና ፡ ልብሳቸውን ፡ ሲወረውሩ ፡ ትቢያ
፳፬ ንም ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ሲበትኑ ፥ የሻለቃው ፡ ወደ ፡
ሰፈሩ ፡ እንዲያገቡት ፡ አዘዘ ፤ እንደዚህም ፡ የጮ
ኹበትን ፡ ምክንያት ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፡— እየገ
፳፭ ረፉችሁ ፡ መርምሩት ፡ አላቸው ። በጠፍርም ፡
በገተሩት ፡ ጊዜ ፡ ጳውሎስ ፡ በአጠገቡ ፡ የቆመ
ውን ፡ የመቶ ፡ አለቃ ፡— የሮማዊን ፡ ሰው ፡ ያለ ፡
ፍርድ ፡ ትገርፉ ፡ ዘንድ ፡ ተፈቅዶላችኋልን ?
፳፮ አለው ። የመቶ ፡ አለቃውም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡
ወደ ፡ ሻለቃው ፡ ቀርቦ ፡— ይህ ፡ ሰው ፡ ሮማዊ ፡
ነውና ፡ ታደርገው ፡ ዘንድ ፡ ካለህ ፡ ተጠበቅ ፡
፳፯ ብሎ ፡ ነገረው ። የሻለቃውም ፡ ቀርቦ ፡— አንተ ፡
ሮማዊ ፡ ነህን ? ንገረኝ ፡ አለው ፤ እርሱም ፡—
፳፰ አዎን ፡ አለ ። የሻለቃውም ፡ መልሶ ፡— እኔ ፡
ይህን ፡ ዜግነት ፡ በብዙ ፡ ገንዘብ ፡ አገኘሁት ፡
አለ ። ጳውሎስም ፡— እኔ ፡ ግን ፡ በእርስዋ ፡ ተወ
፳፱ ለድሁ ፡ አለ ። ስለዚህም ፡ ሊመረምሩት ፡ ያሰ
ቡት ፡ ከእርሱ ፡ ወዲያው ፡ ተለዩ ፤ የሻለቃውም ፡
ደግሞ ፡ ሮማዊ ፡ መሆኑን ፡ ባወቀ ፡ ጊዜ ፡ ፈራ ፥
አስሮት ፡ ነበርና ።
፴ በማግሥቱም ፡ አይሁድ ፡ የከሰሱት ፡ በምን ፡
ምክንያት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እርግጡን ፡ ያውቅ ፡
ዘንድ ፡ አሰበ ፡ ፈታው ፥ የካህናት ፡ አለቆችና ፡
ሸንጎውም ፡ ሁሉ ፡ ይሰበሰቡ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፥
ጳውሎስንም ፡ አውርዶ ፡ በፊታቸው ፡ አቆ
መው ።

ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩ ጳውሎስም ፡ ሸንጎውን ፡ ትኩር ፡ ብሎ ፡ ተመ
ልክቶ ፡— ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ እኔ ፡ እስከዚች ፡
ቀን ፡ ድረስ ፡ በመልካም ፡ ሕሊና ፡ ሁሉ ፡ በእግ
፪ ዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ኖሬአለሁ ፡ አለ ። ሊቀ ፡ ካህ
ናቱም ፡ ሐናንያ ፡ አፉን ፡ ይመቱት ፡ ዘንድ ፡ በአ
፫ ጠገቡ ፡ ቆመው ፡ የነበሩትን ፡ አዘዘ ። በዚያን ፡
ጊዜ ፡ ጳውሎስ ፡— አንተ ፡ በኖራ ፡ የተለሰነ ፡ግድ
ግዳ ፥ እግዚአብሔር ፡ አንተን ፡ ይመታ ፡ ዘንድ ፡
አለው ፤ አንተ ፡ በሕግ ፡ ልትፈርድብኝ ፡ ተቀ
ምጠህ ፡ ሳለህ ፡ ያለ ፡ ሕግ ፡ እመታ ፡ ዘንድ ፡ ታዝ
፬ ለህን ? አለው ። በአጠገቡ ፡ የቆሙትም ፡—
የእግዚአብሔርን ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ ትሳደባለህን ?
፭ አሉት ። ጳውሎስም ፡— ወንድሞች ፡ ሆይ ፥
ሊቀ ፡ ካህናት ፡ መሆኑን ፡ ባላውቅ ፡ ነው ፤ በሕ
ዝብህ ፡ አለቃ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ቃል ፡ አትናገር ፡
ተብሎ ፡ ተጽፎአልና ፡ አላቸው ።
፮ ጳውሎስ ፡ ግን ፡ እኵሌቶቹ ፡ ሰዱቃውያን ፡
እኵሌቶቹም ፡ ፈሪሳውያን ፡ መሆናቸውን ፡
አይቶ ፡— ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ እኔ ፡ ፈሪሳዊ ፡
የፈሪሳዊም ፡ ልጅ ፡ ነኝ ፤ ስለ ፡ ተስፋና ፡ ስለ ፡
ሙታን ፡ መነሣት ፡ ይፈረድብኛል ፡ ብሎ ፡ በሸ
፯ ንጎው ፡ ጮኸ ። ይህንም ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ በፈሪሳ
ውያንና ፡ በሰዱቃውያን ፡ መካከል ፡ ጥል ፡ ሆነ ፡
፰ ሸንጎውም ፡ ተለያየ ። ሰዱቃውያን ፡— ትንሣ
ኤም ፡ መልአክም ፡ መንፈስም ፡ የለም ፡ የሚሉ ፡
ናቸውና ፤ ፈሪሳውያን ፡ ግን ፡ ሁለቱን ፡ ያም
፱ ናሉ ። ታላቅ ፡ ጩኸትም ፡ ሆነ ፥ ከፈሪሳው
ያንም ፡ ወገን ፡ የሆኑት ፡ ጻፎች ፡ ተነሥተው ፡—
በዚህ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ምንም ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አላገ
ኘንበትም ፤ መንፈስ ፡ ወይስ ፡ መልአክ ፡ ተና
፲ ግሮት ፡ ይሆን ? ብለው ፡ ተከራከሩ ። ብዙ ፡
ጥልም ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ የሻለቃው ፡ ጳውሎስን ፡
እንዳይገነጣጥሉት ፡ ፈርቶ ፡ጭፍሮቹ ፡ ወርደው ፡
ከመካከላቸው ፡ እንዲነጥቁት ፡ ወደ ፡ ሰፈሩም ፡
እንዲያገቡት ፡ አዘዘ ።
፲፩ በሁለተኛውም ፡ ሌሊት ፡ ጌታ ፡ በአጠገቡ ፡
ቆሞ ፡— ጳውሎስ ፡ ሆይ ፥ በኢየሩሳሌም ፡ ስለ ፡
እኔ ፡ እንደ ፡ መሰከርህ ፡ እንዲሁ ፡ በሮሜም ፡
ትመሰክርልኝ ፡ ዘንድ ፡ ይገባሃልና ፡ አይዞህ ፡
አለው ።
፲፪ በነጋም ፡ ጊዜ ፡ አይሁድ ፡ ጳውሎስን ፡ እስኪ
ገድሉት ፡ ድረስ ፡ እንዳይበሉና ፡ እንዳይጠጡ ፡
፲፫ በመሐላ ፡ ተስማሙ ። ይህንም ፡ ሴራ ፡ ያደረ
፲፬ ጉት ፡ ሰዎች ፡ ከአርባ ፡ ይበዙ ፡ ነበር ፤ እነርሱም ፡
ወደ ፡ ካህናት ፡ አለቆችና ፡ ወደ ፡ ሽማግሌዎቹ ፡
መጥተው ፡— ጳውሎስን ፡ እስክንገድል ፡ ድረስ ፡
ምንም ፡ እንዳንቀምስ ፡ ተረግመን ፡ ተማምለ
፲፭ ናል ። እንግዲህ ፡ አሁን ፡ እናንተ ፡ ከሸንጎው ፡
ጋር ፡ ሆናችሁ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ አጥብቃችሁ ፡
እንደምትመረምሩ ፡ መስላችሁ ፥ ወደ ፡ እናንተ ፡
እንዲያወርደው ፡ ለሻለቃው ፡ አመልክቱት ፤
እኛም ፡ ሳይቀርብ ፡ እንድንገድለው ፡ የተዘጋጀን ፡
ነን ፡ አሉአቸው ።
፲፮ የጳውሎስ ፡ የእኅቱ ፡ ልጅ ፡ ግን ፡ ደባቸውን ፡
በሰማ ፡ ጊዜ ፥ መጥቶ ፡ ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ ገባና ፡ ለጳው
፲፯ ሎስ ፡ ነገረው ። ጳውሎስም ፡ ከመቶ ፡ አለቆች ፡ አን
ዱን ፡ ጠርቶ ፡— ይህን ፡ ብላቴና ፡ ወደ ፡ ሻለቃው ፡
ውሰድ ፥ የሚያወራለት ፡ ነገር ፡ አለውና ፡ አለው ።
፲፰ እርሱም ፡ ይዞት ፡ ወደ ፡ ሻለቃው ፡ ወስደውና ፡—
ይህ ፡ ብላቴና ፡ የሚነግርህ ፡ ነገር ፡ ስላለው ፡ አስ

[illegible]

ረኛው ፡ ጳውሎስ ፡ ጠርቶ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እንድ
፲፱ ወስደው ፡ ለመነኝ ፡ አለው ። የሻለቃውም ፡
እጁን ፡ ይዞ ፡ ፈቀቅ ፡ አለና ፡ ለብቻው ፡ ሆኖ ፡—
የምታወራልኝ ፡ ነገር ፡ ምንድር ፡ ነው ? ብሎ ፡
፳ ጠየቀው ። እርሱም ፡— አይሁድ ፡ ስለ ፡ ጳው
ሎስ ፡ ከፊት ፡ ይልቅ ፡ አጥብቀህ ፡ እንደምትመ
ረምር ፡ መስለህ ፥ ነገ ፡ ወደ ፡ ሸንጎ ፡ ታወርደው ፡
፳፩ ዘንድ ፡ ሊለምኑህ ፡ ተስማምተዋል ። እንግዲህ ፡
አንተ ፡ በጅ ፡ አትበላቸው ፤ እስኪገድሉት ፡
ድረስ ፡ እንዳይበሉና ፡ እንዳይጠጡ ፡ ተማም
ለው ፡ ከእነርሱ ፡ ከአርባ ፡ የሚበዙ ፡ ሰዎች ፡ ያደቡ
በታልና ፤ አሁንም ፡ የተዘጋጁ ፡ ናቸው ፡ የአን
፳፪ ተንም ፡ ምላሽ ፡ ይጠብቃሉ ፡ አለው ። የሻለቃ
ውም ፡— ይህን ፡ ነገር ፡ ለእኔ ፡ ማመልከትህን ፡
ለማንም ፡ እንዳትገልጥ ፡ ብሎ ፡ ከዘዘ ፡ በኋላ ፡
ብላቴናውን ፡ አሰናበተው ።

፳፫ ከመቶ ፡ አለቆቹም ፡ ሁለት ፡ ጠርቶ ፡— ወደ ፡
ቂሣርያ ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ወታደ
ሮችንና ፡ ሰባ ፡ ፈረሰኞችን ፡ ሁለት ፡ መቶም ፡
ባለ ፡ ጦር ፡ መሣሪያዎችን ፡ ከሌሊቱ ፡ በሦስተ
፳፬ ኛው ፡ ሰዓት ፡ አዘጋጁ ፡ አላቸው ። ጳውሎስ
ንም ፡ ወደ ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ወደ ፡ ፊልክስ ፡ በደኅና ፡
እንዲያደርሱት ፡ የሚያስቀምጡበትን ፡ ከብት ፡
፳፭ ያዘጋጁ ፡ ዘንድ ፡ አዘዛቸው ። ደብዳቤም ፡ ጻፈ ፡
እንዲህ ፡ የሚል ፡—

፳፮ ከቀላውዴዎስ ፡ ሉስዮስ ፡ ወደ ፡ ክቡር ፡ አገረ ፡
ገዥ ፡ ወደ ፡ ፊልክስ ፤ ሰላም ፡ ለአንተ ፡ ይሁን ።
፳፯ ይህን ፡ ሰው ፡ አይሁድ ፡ ይዘው ፡ ሊገድሉት ፡
ባሰቡ ፡ ጊዜ ፡ ከጭፍሮቼ ፡ ጋር ፡ ደርሼ ፡ አዳን
ሁት ፥ ሮማዊ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አውቄ ፡ ነበርና ።
፳፰ የሚከሰሱበትንም ፡ ምክንያት ፡ አውቅ ፡ ዘንድ ፡
፳፱ አለቤ ፡ ወደ ፡ ሸንጎአቸው ፡ አወረድሁት ፤ በሕ
ጋቸውም ፡ ስለ ፡ መከራከር ፡ እንደ ፡ ከሰሱት ፡
አገኘሁ ፡ እንጂ ፡ ለሞት ፡ ወይም ፡ ለእስራት ፡
፴ የሚያደርስ ፡ ክስ ፡ አይደለም ። በዚህም ፡ ሰው ፡
አይሁድ ፡ ሴራ ፡ እንዲያደርጉበት ፡ በመለከ
ቱኝ ፡ ጊዜ ፡ ያን ፡ ጊዜውን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ሰደ
ድሁት ፥ ከሳሾቹንም ፡ ደግሞ ፡ በፊትህ ፡ ይከ
ሱት ፡ ዘንድ ፡ አዘዝኋቸው ። ደኅና ፡ ሁን ።

፴፩ ወታደሮቹም ፡ እንደ ፡ ታዘዙት ፡ ጳውሎስን ፡
ይዘው ፡ በሌሊት ፡ ወደ ፡ አንቲጳጥሪስ ፡ አደረ
፴፪ ሱት ፤ በነገውም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡
ፈረሰኞችን ፡ ትተው ፡ ወደ ፡ ሰፈር ፡ ተመለሱ ።
፴፫ እነዚያም ፡ ወደ ፡ ቂሣርያ ፡ ገብተው ፡ ደብዳቤ
ውን ፡ ለአገረ ፡ ገዥ ፡ በሰጡ ፡ ጊዜ ፡ ጳውሎ
፴፬ ስን ፡ ደግሞ ፡ በፊቱ ፡ አቆሙት ። ካነበበውም ፡
በኋላ ፡ የወዲት ፡ አውራጃ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ጠየ
ቀው ፤ የኪልቅያ ፡ ሰው ፡ መሆኑንም ፡ በወቀ ፡
፴፭ ጊዜ ፡— ከሳሾችህ ፡ ደግሞ ፡ ሲመጡ ፡ እሰማሃ
ለሁ ፡ አለው ፤ በሄሮድስም ፡ ግቢ ፡ ውስጥ ፡ ይጠ
ብቁት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።

ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ ከአምስት ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ሊቀ ፡ ካህናቱ ፡
ሐናንያ ፡ ከሽማግሌዎችና ፡ ጠርጠሉስ ፡ ከሚ
ሉት ፡ ከአንድ ፡ ጠበቃ ፡ ጋር ፡ ወረደ ፤ እነርሱም ፡
ስለ ፡ ጳውሎስ ፡ ለአገረ ፡ ገዥ ፡ አመለከቱት ።
፪ በተጠራም ፡ ጊዜ ፡ ጠርጠሉስ ፡ ይከሰው ፡ ዘንድ ፡
ጀመረ ፡ እንዲህ ፡ አያለ ፡—

ክቡር ፡ ፊልክስ ፡ ሆይ ፥ በአንተ ፡ በኩል ፡ ብዙ ፡
ሰላም ፡ ስለምናገኝ ፡ ስለዚህም ፡ ሕዝብ ፡ በአሳብህ ፡
በየነገሩ ፡ በየስፍራውም ፡ መልካም ፡ መሻሻል ፡
፫ ስለሚሆንለት ፥ በፍጹም ፡ ምስጋና ፡ እንቀበለዋ
ለን ። ነገር ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ እንዳላቆይህ ፡ በቸርነ
፬ ትህ ፡ በአጭሩ ፡ ትሰማን ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ።
፭ ይህ ፡ ሰው ፡ በሽታ ፡ ሆኖ ፡ በዓለም ፡ ባሉት ፡ አይ
ሁድ ፡ ሁሉ ፡ ሁከት ፡ ሲያስነሣ ፥ የመናፍቃን ፡
የናዝራውያን ፡ ወገን ፡ መሪ ፡ ሆኖ ፡ አግኝተነዋ
፮ ልና ፤ መቅደስንም ፡ ደግሞ ፡ ሊያረክስ ፡ ሲሞ
ክር ፡ ያዝነው ፥ እንደ ፡ ሕጋችንም ፡ እንፈርድ
፯ በት ፡ ዘንድ ፡ወደድን ። ነገር ፡ ግን ፡ የሻለቃው ፡
ሉስዮስ ፡ መጥቶ ፡ በብዙ ፡ ኃይል ፡ ከእጃችን ፡
፰ ወሰደው ፥ ከሳሾቹንም ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ይመጡ ፡
ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ አንተም ፡ ራስህ ፡ እርሱን ፡ መር
ምረህ ፡ እኛ ፡ ስለምንከስበት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ልታ
ውቅ ፡ ትችላለህ ።

፱ አይሁድም ፡ ደግሞ ፡— ይህ ፡ ነገር ፡ እንዲሁ ፡
ነው ፡ እያሉ ፡ ተስማሙ ።

፲ ገዥም ፡ በጠቀሰው ፡ ጊዜ ፡ ጳውሎስ ፡ መለሰ ፡
እንዲህ ፡ ሲል ፡—

ከብዙ ፡ ዘመን ፡ ጀምረህ ፡ ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ አንተ ፡
ፈራጅ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ አውቃለሁና ፡ ደስ ፡ እያ
፲፩ ለኝ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ ነገር ፡ እመልሳለሁ ፤ እሰግድ ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ከወጣሁ ፡ ከአሥራ ፡
ሁለት ፡ ቀን ፡ እንዳይበልጥ ፡ ልታውቀው ፡ ትች
፲፪ ላለህ ። ከአንድም ፡ ሰንኳ ፡ ስነጋገር ፡ ወይም ፡
ሕዝብን ፡ ስሰበስብ ፡ በመቅደስ ፡ ቢሆን ፡ በምኵ
ራብም ፡ ቢሆን ፡ በከተማም ፡ ቢሆን ፡ አላገኙ
፲፫ ኝም ። አሁንም ፡ ስለሚከሱኝ ፡ ያስረዱህ ፡
፲፬ ዘንድ ፡ አይችሉም ። ነገር ፡ ግን ፡ ይህን ፡ እመሰከ
ርልሃለሁ ፤ በሕጉ ፡ ያለውን ፡ በነቢያትም ፡ የተጻ
ፉትን ፡ ሁሉ ፡ አምኜ ፥ የአባቶቼን ፡ አምላክ ፡ እነ
ርሱ ፡ ኑፋቄ ፡ ብለው ፡ እንደሚጠሩት ፡ መንገድ ፡
፲፭ አመልከዋለሁ ፤ እነዚህም ፡ ራሳቸው ፡ ደግሞ ፡
የሚጠብቁት ፥ ጻድቃንም ፡ ዓመፀኞችም ፡ ከሙ
ታን ፡ ይነሡ ፡ ዘንድ ፡ እንዳላቸው ፡ ተስፋ ፡ በእ
፲፮ ግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ አለኝ ። ስለዚህ ፡ እኔ ፡
ደግሞ ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ ሁል
ጊዜ ፡ ነውር ፡ የሌለበት ፡ ሕሊና ፡ ትኖረኝ ፡ ዘንድ ፡
፲፯ እተጋለሁ ። ከብዙ ፡ ዓመትም ፡ በኋላ ፡ ለሕ
ዝቤ ፡ምጽዋትና ፡ መሥዋዕት ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡
፲፰ መጣሁ ፤ ይህንም ፡ ሳደርግ ፡ ሳለሁ ፡ ሕዝብ ፡ ሳይ
ሰበሰብ ፡ ሁከትም ፡ ሳይሆን ፡ በመቅደስ ፡ ስነጻ ፡

፳፫ ። ፳፮ ፤ ም. ፳፩ ፥ ፴—፴፪ ፤ ፳፪ ፥ ፳፯ ። ፳፰ ፤ ም. ፳፪ ፥ ፴ ።

፳፬ ። ፩ ፤ ም. ፳፫ ፥ ፪ ። ፭ ፤ ም. ፲፯ ፥ ፯ ፥ ፲ ። ፲፭ ፤ ዳን. ፲፪ ፥ ፪ ።

፲፱ አገኙኝ ። ነገር ፡ ግን ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ነገር ፡ ያላ
ቸው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ በፊትህ ፡ መጥተው ፡ ይከሱኝ ፡
ዘንድ ፡ የሚገባቸው ፡ ከእስያ ፡ የመጡ ፡ አንዳ
፳ ንድ ፡ አይሁድ ፡ አሉ ። ወይም ፡ በመካከላቸው ፡
ቆሜ ፦ ዛሬ ፡ ስለ ፡ ሙታን ፡ መነሣት ፡ በፊታ
ችሁ ፡ በእኔ ፡ ይፈርዱብኛል ፡ ብዬ ፡ ከጮኽሁት ፡
ከዚህ ፡ ከአንድ ፡ ነገር ፡ በቀር ፥ በሸንጎ ፡ ፊት ፡
ቆሜ ፡ ሳለሁ ፡ በእኔ ፡ አንድ ፡ ዓመፃ ፡ ያገኙ ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ እነዚህ ፡ ራሳቸው ፡ ይናገሩ ።

፳፪ ፊልክስ ፡ ግን ፡ የመንገዱን ፡ ነገር ፡ አጥብቆ ፡
አውቆአልና ፦ የሻለቃው ፡ ሉስዮስ ፡ በወረደ ፡
ጊዜ ፡ ነገራችሁን ፡ አቈርጣለሁ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡
፳፫ አዘገያቸው ። የመቶውንም ፡ አለቃ ፡ ጳውሎ
ስን ፡ ሲጠብቅ ፡ እንዲያደላለት ፥ ከወዳጆቹም ፡
ማንም ፡ ሲያገለግለው ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡
ሲመጣ ፡ እንዳይከለክልበት ፡ አዘዘው ።

፳፬ ከጥቂት ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ፊልክስ ፡ አይሁዳ
ዊት ፡ ከነበረች ፡ ድሩሲላ ፡ ከሚሉአት ፡ ከሚስቱ ፡
ጋር ፡ መጥቶ ፡ ጳውሎስን ፡ አስመጣ ፥ በኢየሱስ
ክርስቶስም ፡ ስለ ፡ ማመን ፡ የሚናገረውን ፡
፳፭ ሰማው ። እርሱም ፡ ስለ ፡ ጽድቅና ፡ ራስን ፡ ስለ ፡
መግዛት ፡ ስለሚመጣውም ፡ ኵነኔ ፡ ሲነጋገር ፡
ሳለ ፥ ፊልክስ ፡ ፈርቶ ፦ አሁንስ ፡ ሂድ ፥ በተ
መቸኝም ፡ ጊዜ ፡ ልኬ ፡ አስጠራሃለሁ ፡ ብሎ ፡
፳፮ መለሰለት ። ያን ፡ ጊዜም ፡ ደግሞ ፡ እንዲፈታው ፡
ጳውሎስ ፡ ገንዘብ ፡ ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡
አደረገ ፤ ስለዚህ ፡ ደግሞ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ እያስ
፳፯ መጣ ፡ ያነጋግረው ፡ ነበር ። ሁለት ፡ ዓመትም ፡
ከሞላ ፡ በኋላ ፡ ጶርቅዮስ ፡ ፊስጦስ ፡ በፊልክስ ፡
ፈንታ ፡ ተተካ ። ፊልክስም ፡ አይሁድን ፡ ደስ ፡
ያሰኝ ፡ ዘንድ ፡ ወዶ ፡ ጳውሎስን ፡ እንደ ፡ታሰረ ፡
ተወው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

፩ ፊስጦስም ፡ ወደ ፡ አውራጃው ፡ ገብቶ ፡ ከሦ
ስት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ከቂሣርያ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳ
፪ ሌም ፡ ወጣ ። የካህናቱ ፡ አለቆችና ፡ የአይሁ
ድም ፡ታላላቆች ፡ በጳውሎስ ፡ ላይ ፡ አመለከቱ ፥
፫ ጳውሎስንም ፡ ሲቃወም ፡ እንዲያደላላቸው ፡
እየለመኑ ፥ በመንገድ ፡ ሸምቀው ፡ ይገድሉት ፡
ዘንድ ፡ አስበው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እንዲያስ
፬ መጣው ፡ ማለዱት ። ፊስጦስ ፡ ግን ፡ ጳውሎስ ፡
በቂሣርያ ፡ እንዲጠበቅ ፡ እርሱም ፡ ራሱ ፡ ወደ
ዚያ ፡ ፈጥኖ ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ እንዳለው ፡ መለሰ
፭ ላቸው ፤ እንግዲህ ፡ በዚህ ፡ ሰው ፡ ክፉት ፡ ቢሆን ፡
ከእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ያሉት ፡ በለ ፡ ሥልጣኖች ፡
ከእኔ ፡ ጋር ፡ ወርደው ፡ ይክሰሱት ፡ አላቸው ።

፮ በእነርሱም ፡ ዘንድ ፡ ከስምንት ፡ ወይም ፡ ከአ
ሥር ፡ የማይበልጥ ፡ ቀን ፡ ተቀምጦ ፡ ወደ ፡ ቂሣ
ርያ ፡ ወረደ ፤ በነገውም ፡ በፍርድ ፡ ወንበር ፡
ተቀምጦ ፡ ጳውሎስን ፡ያመጡት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።
፯ በቀረበም ፡ ጊዜ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ የወረዱት ፡
አይሁድ ፡ከበውት ፡ቆሙ ፥ ይረቱበትም ፡ ዘንድ ፡
የማይችሉትን ፡ ብዙና ፡ ከበድ ፡ ክስ ፡ አነሡበት ፤
፰ ጳውሎስም ፡ ሲምዋገት ፦ የአይሁድን ፡ ሕግ ፡
ቢሆን ፡ መቅደስንም ፡ ቢሆን ፡ ቄሣርንም ፡ ቢሆን ፡
፱ አንዳች ፡ ስንኳ ፡ አልበደልሁም ፡ አለ ። ፊስ
ጦስ ፡ ግን ፡ አይሁድን ፡ደስ ፡ ያሰኝ ፡ ዘንድ ፡ ወዶ ፡
ጳውሎስን ፦ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወጥተህ ፡
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ከዚያው ፡ በፊቴ ፡ ትፋረድ ፡
፲ ዘንድ ፡ ትወዳለህን ? ብሎ ፡ መለሰለት ። ጳው
ሎስ ፡ ግን ፦ እፋረድበት ፡ ዘንድ ፡ በሚገባኝ ፡
በቄሣር ፡ ፍርድ ፡ ወንበር ፡ ፊት ፡ ቆሜአለሁ ።
አንተው ፡ ደግሞ ፡ ፈጽመህ ፡ እንደምታውቅ ፡
፲፩ አይሁድን ፡ ምንም ፡ አልበደልሁም ። እንግዲህ ፡
በድዬ ፡ ወይም ፡ ሞት ፡ የሚገባውን ፡ ነገር ፡ አድ
ርጌ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከሞት ፡ ልዳን ፡ አልልም ፤
እነዚህ ፡ የሚከሱኝ ፡ ክስ ፡ ከንቱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ግን ፡ ለእነርሱ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጠኝ ፡ ዘንድ ፡
ማንም ፡ አይችልም ፤ ወደ ፡ ቄሣር ፡ ይግባኝ ፡
፲፪ ብዬአለሁ ፡ አለ ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ፊስጦስ ፡ ከአ
ማካሪዎቹ ፡ ጋር ፡ ተማክሮ ፦ ወደ ፡ ቄሣር ፡
ይግባኝ ፡ ብለሃል ፤ ወደ ፡ ቄሣር ፡ ትሄዳለህ ፡
ብሎ ፡ መለሰለት ።

፲፫ ከጥቂት ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ንጉሡ ፡ አግሪጳ ፡
በርኒቄም ፡ ለፊስጦስ ፡ ሰላምታ ፡ እንዲያቀርቡ ፡
፲፬ ወደ ፡ ቂሣርያ ፡ ወረዱ ። በዚያውም ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡
ስለ ፡ ተቀመጡ ፡ ፊስጦስ ፡ የጳውሎስን ፡ ነገር ፡
ለንጉሡ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ገለጠ ፦ ፊልክስ ፡
እስር ፡ የተወው ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ በዚህ ፡ አለ ፤
፲፭ በኢየሩሳሌምም ፡ ሳለሁ ፡ የካህናት ፡ አለቆችና ፡
የአይሁድ ፡ ሽማግሌዎች ፡ እፈርድበት ፡ ዘንድ ፡
፲፮ እየለመኑ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ አመለከቱኝ ። እኔም ፦
ተከሳሹ ፡ በከሳሾቹ ፡ ፊት ፡ ሰፊት ፡ ሳይቆም ፡
ለተከሰሰበትም ፡ መልስ ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ፈንታ ፡
ሳያገኝ ፥ ማንንም ፡ ቢሆን ፡ አሳልፎ ፡ መስጠት ፡
የሮማውያን ፡ ሥርዓት ፡ አይደለም ፡ ብዬ ፡ መለስ
፲፯ ሁላቸው ። ስለዚህም ፡ በዚህ ፡ በተሰበሰቡ ፡
ጊዜ ፥ ሳልዘገይ ፡ በማግሥቱ ፡ በፍርድ ፡ ወንበር ፡
ተቀምጬ ፡ ያንን ፡ ሰው ፡ ያመጡት ፡ ዘንድ ፡ አዘ
፲፰ ዝሁ ። ከሳሾቹም ፡ በቆሙ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ ያሰብ
ሁትን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ክስ ፡ ምንም ፡ አላመጡበ
፲፱ ትም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ገዛ ፡ሃይማኖታቸውና ፡
ጳውሎስ ፦ ሕያው ፡ ነው ፡ ስለሚለው ፡ ስለ ፡
ሞተው ፡ ኢየሱስ ፡ ስለ ፡ ተባለው ፡ ከእርሱ ፡
፳ ጋር ፡ ይከራከሩ ፡ ነበር ። እኔም ፡ ይህን ፡ ነገር ፡
እንዴት ፡ እንድመረምር ፡ አመንትቼ ፦ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ሄደህ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ከዚያ ፡ ልት
፳፩ ፋረድ ፡ ትወዳለህን ? አልሁት ። ጳውሎስ ፡ ግን ፡
አውግስጦስ ፡ ቄሣር ፡ እስኪቈርጥ ፡ ድረስ ፡ እን
ዲጠበቅ ፡ ይግባኝ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፥ ወደ ፡ ቄሣር ፡
እስክሰደው ፡ ድረስ ፡ ይጠበቅ ፡ ዘንድ ፡ አዘዝሁ ።
፳፪ አግሪጳም ፡ ፊስጦስን ፦ ያንንስ ፡ ሰው ፡ እኔ ፡
ደግሞ ፡ እኮ ፡ እሰማው ፡ ዘንድ ፡ እወድ ፡ ነበር ፡

፳፬ ፡ ፳፮ ፡ ምዕ ፳፫ ፥ ፮ ። ፳፯ ፤ ሚክ ፯ ፥ ፫ ።
፳፭ ። ፯ ፤ ምዕ ፳፬ ፥ ፭ ። ፲፩ ፤ ምዕ ፱ ፥ ፲፭ ።

አለው ። እርሱም ፡— ነገ ፡ ትሰማዋለህ ፡ አለው ።

፳፫ በነገውም ፡ አግሪጳና ፡ በርኒቄ ፡ በብዙ ፡ ግርማ ፡ መጥተው ፡ ከሻለቆችና ፡ ከከተማው ፡ ታላላቆች ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ፍርድ ፡ ቤት ፡ ገቡ ፤ ፊስጦስም ፡ ፳፬ በዘዘ ፡ ጊዜ ፡ ጳውሎስን ፡ አመጡት ። ፊስጦስም ፡ አለ ፡— አግሪጳ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፡ እናንተም ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ያላችሁ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፥ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ በሕይወት ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ እንዳይገባው ፡ እየጮኹ ፡ የአይሁድ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በዚህም ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ የለመኑ ፳፭ ኝን ፡ ይህን ፡ ሰው ፡ ታዩታላችሁ ። እኔ ፡ ግን ፡ ሞት ፡ የሚገባውን ፡ ነገር ፡ እንዳላደረገ ፡ አስተዋልሁ ፥ እርሱም ፡ ወደ ፡ አውግስጦስ ፡ ይግባኝ ፡ ፳፮ ስላለ ፡ እሰደው ፡ ዘንድ ፡ ቈረጥሁ ። ስለ ፡ እርሱም ፡ ወደ ፡ ጌታዬ ፡ የምጽፈው ፡ እርግጥ ፡ ነገር ፡ የለኝም ፤ ስለዚህ ፡ ከተመረመረ ፡ በኋላ ፡ የምጽፈውን ፡ ነገር ፡ አገኝ ፡ ዘንድ ፡ በፊታችሁ ፡ ይልቁንም ፡ በፊትህ ፥ ንጉሥ ፡ አግሪጳ ፡ ሆይ ፥ ፳፯ አመጣሁት ፤ እስረኛ ፡ ሲላክ ፡ የተከሰሰበትን ፡ ምክንያት ፡ ደግሞ ፡ አለማመልከት ፡ ምኝነት ፡ መስሎኛልና ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩ አግሪጳም ፡ ጳውሎስን ፡— ስለ ፡ ራስህ ፡ ትናገር ፡ ዘንድ ፡ ተፈቅዶልሃል ፡ አለው ። በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ጳውሎስ ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡ መለስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡—

፪፡፫ ንጉሥ ፡ አግሪጳ ፡ ሆይ ፥ የአይሁድን ፡ ሥርዓት ፡ ክርክርንም ፡ ሁሉ ፡ አጥብቀህ ፡ አውቀሃልና ፡ በአይሁድ ፡ በተከሰስሁበት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ዛሬ ፡ በፊትህ ፡ ስለምመልስ ፡ ራሴን ፡ እጅግ ፡ እንደ ፡ ተመረቀ ፡ አድርጌ ፡ እቈጥረዋለሁ ፤ ስለዚህ ፡ በትዕግሥት ፡ ትሰማኝ ፡ ዘንድ ፡ እለምንሃለሁ ።

፬ ከመጀመሪያ ፡ አንሥቶ ፡ በሕዝቤ ፡ መካከል ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሆነውን ፥ ከታናሽነቴ ፡ጀምሬ ፡ የኖርሁትን ፡ ኑሮዬን ፡ አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ ያው ፭ ቃሉ ፤ ሊመሰክሩ ፡ ይወዱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ በአምልኮአችን ፡ ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ሕግን ፡ በመጠንቀቅ ፡ እንደሚተጋ ፡ ወገን ፡ ፈሪሳዊ ፡ ሆኜ ፡ እንደ ፡ ኖርሁ ፡ ከጥንት ፡ ጀምረው ፡ አውቀውኛልና ።

፮ አሁንም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ለአባቶቻችን ፡ ስለ ፡ ተሰጠው ፡ ስለ ፡ ተስፋ ፡ ቃል ፡ አለ ፯ ኝታ ፡ ልፋረድ ፡ ቆሜአለሁ ። ወደዚህም ፡ ወደ ፡ ተስፋ ፡ ቃል ፡ አሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ወገኖቻችን ፡ ሌሊትና ፡ ቀን ፡ በትጋት ፡ እያመለኩ ፡ ይደርሱ ፡ ዘንድ ፡ አለኝታ ፡ አላቸው ፤ ስለዚህም ፡ አለኝታ ፥ ንጉሥ ፡ አግሪጳ ፡ ሆይ ፥ ከአይሁድ ፡ እከ ፰ ሰሰሁ ። እግዚአብሔር ፡ ሙታንን ፡ የሚያስነሣ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ የማይታመን ፡ ነገር ፡ ሆኖ ፡ ይቈጠራል ?

፱ እኔም ፡ ራሴ ፡ የናዝሬቱን ፡ የኢየሱስን ፡ ስም ፡ የሚቃወም ፡ እጅግ ፡ ነገር ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ እንዲገባኝ ፡ ይመስለኝ ፡ ነበር ። ፲ ይህንም ፡ ደግሞ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አደረግሁት ፤ ከካህናት ፡ አለቆችም ፡ ሥልጣን ፡ ተቀብዬ ፡ እኔ ፡ ከቅዱሳን ፡ ብዙዎችን ፡ በወኅኒ ፡ አሳሰርኋቸው ፥ ሲገድሉአቸውም ፡ አብሬ ፡ ተቸሁ ። ፲፩ በምኵራብም ፡ ሁሉ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ እየቀጣሁ ፡ ይሰድቡት ፡ ዘንድ ፡ ግድ ፡ አልኋቸው ፤ ያለ ፡ ልክ ፡ ስቈጣባቸውም ፡ እስከ ፡ ውጭ ፡ አገር ፡ ከተማዎች ፡ ድረስ ፡ እንኳ ፡ አሳድድ ፡ ነበር ።

፲፪ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ከካህናት ፡ አለቆች ፡ ሥልጣንና ፡ ትእዛዝ ፡ ተቀብዬ ፡ ወደ ፡ ደማስቆ ፡ ስሄድ ፥ ፲፫ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ በመንገድ ፡ ሳለሁ ፡ እኩል ፡ ቀን ፡ ሲሆን ፡ በዙሪያዬና ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ በሄዱት ፡ ዙሪያ ፡ ከፀሐይ ፡ ብሩህነት ፡ የበለጠ ፡ ብርሃን ፡ ከሰማይ ፡ ሲበራ ፡ አየሁ ፤ ፲፬ ሁላችንም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በወደቅን ፡ ጊዜ ፡— ሳውል ፡ ሳውል ፥ ስለ ፡ ምን ፡ ታሳድደኛለህ ? የመውጊያውን ፡ ብረት ፡ ብትቃወም ፡ ለአንተ ፡ ይብስብሃል ፡ የሚል ፡ ድምፅ ፡ በዕብራይስጥ ፡ ቋንቋ ፡ ሲናገረኝ ፡ ሰማሁ ። ፲፭ እኔም ፡— ጌታ ፡ ሆይ ፥ ማን ፡ ነህ ? አልሁ ። እርሱም ፡ አለኝ ፡— አንተ ፡ የምታሳድደኝ ፡ እኔ ፡ ኢየሱስ ፡ ነኝ ። ፲፮ ነገር ፡ ግን ፡ ተነሣና ፡ በእግርህ ፡ ቁም ፤ ስለዚህ ፡ እኔን ፡ በየህበት ፡ ነገር ፡ ለአንተም ፡ በምታይበት ፡ ነገር ፡ አገልጋይና ፡ ምስክር ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ልሾምህ ፡ ታይቼልሃለሁና ። ፲፯፡፲፰ የኃጢአትንም ፡ ስርየት ፡ በእኔም ፡ በማመን ፡ በተቀደሱት ፡ መካከል ፡ ርስትን ፡ ያገኙ ፡ ዘንድ ፥ ከጨለማ ፡ ወደ ፡ ብርሃን ፡ ከሰይጣንም ፡ ሥልጣን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘወር ፡ እንዲሉ ፡ ዓይናቸውን ፡ ትከፍት ፡ ዘንድ ፥ ከሕዝቡና ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ከምልክህ ፡ ከአሕዛብ ፡ አድንሃለሁ ።

፲፱ ንጉሥ ፡ አግሪጳ ፡ ሆይ ፥ ስለዚህ ፡ ከሰማይ ፡ የታየኝን ፡ ራእይ ፡ እምቢ ፡ አላልሁም ። ፳ ነገር ፡ ግን ፡ አስቀድሜ ፡ በደማስቆ ፡ ላሉት ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ በይሁዳም ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ለአሕዛብም ፡ ንስሐ ፡ ይገቡ ፡ ዘንድና ፡ ለንስሐ ፡ የሚገባ ፡ ነገር ፡ እያደረጉ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘወር ፡ ይሉ ፡ ዘንድ ፡ ተናገርሁ ። ፳፩ ስለዚህ ፡ አይሁድ ፡ በመቅደስ ፡ ያዙኝ ፡ ሊገድሉኝም ፡ ሞከሩ ። ፳፪፡፳፫ ከእግዚአብሔርም ፡ ዘንድ ፡ ረድኤት ፡ ተቀብዬ ፡ ለታናሹም ፡ ለታላቁም ፡ ስመሰክር ፡ እስከዚች ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ቆሜአለሁ ፤ ነቢያትና ፡ ሙሴ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ያለውን ፥ ክርስቶስ ፡ መከራን ፡ እንዲቀበል ፡ በሙታንም ፡ ትንሣኤ ፡ ለሕዝብና ፡ ለአሕዛብ ፡ ብርሃንን ፡ በመጀመሪያ ፡ ሊሰብክ ፡ እንዳለው ፥ ከተናገሩት ፡ በቀር ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ የተናገርሁት ፡ የለም ።

፳፬ እንዲህም ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ ራሱ ፡ ሲመልስ ፡ ፊስ

፳፮። ፩፤ ማቴ· ፲፥፲፰። ፭፤ ምዕ· ፳፪፥፫። ፱—፲፩፤ ምዕ· ፰፥፩፡፫። ፲፪—፲፰፤ ምዕ· ፱፥፩—፳፤ ፳፪፥፭—፲። ፲፰፤ ፲፰፤ ምዕ· ፳፪፥፲፬፡፲፭፤ ፱፥፲፭። ፲፰፤ ኢሳ· ፵፪፥፯። ፳፩፤ ምዕ· ፳፩፥፴፡፴፩። ፳፪፤ ሉቃ· ፳፬፥፵፬። ፳፫፤ ሉቃ· ፳፬፥፳፮። ፳፬፤ ማር· ፫፥፳፩።

ጦስ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡— ጳውሎስ ፡ ሆይ ፥ አብ ድሃል ፡ እኮ ፤ ብዙ ፡ ትምህርትህ ፡ ወደ ፡ እብ ደት ፡ ያዞርሃል ፡ አለው ። ፳፭ ጳውሎስ ፡ ግን ፡ እን ዲህ ፡ አለ ፡— ክቡር ፡ ፊስጦስ ፡ ሆይ ፥ የእውነት ንና ፡ የአእምሮን ፡ ነገር ፡ እናገራለሁ ፡ እንጂ ፡ እብ ደትስ ፡ የለብኝም ። ፳፮ በእርሱ ፡ ፊት ፡ ደግሞ ፡ በግልጥ ፡ የምናገረው ፡ ንጉሥ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ያውቃል ፤ ከዚህ ፡ ነገር ፡ አንዳች ፡ እንዳይሰወ ርበት ፡ ተረድቼአለሁና ፤ ይህ ፡ በስውር ፡ የተደ ረገ ፡ አይደለምና ። ፳፯ ንጉሥ ፡ አግሪጳ ፡ ሆይ ፥ ነቢ ያትን ፡ ታምናለህን ? እንድታምናቸው ፡ አው ቃለሁ ። ፳፰ አግሪጳም ፡ ጳውሎስን ፡— በጥቂት ፡ ክርስቲያን ፡ ልታደርገኝ ፡ ትወዳለህ ፡ አለው ። ፳፱ ጳውሎስም ፡— በጥቂት ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ በብዙ ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ አይደለህም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ዛሬ ፡ የሚሰሙኝ ፡ ሁሉ ፡ ደግሞ ፡ ከዚህ ፡ እስራት ፡ በቀር ፡ እንደ ፡ እኔ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ እለምናለሁ ፡ አለው ።

፴ ንጉሡም ፡ አገረ ፡ ገዡም ፡ በርኒቄም ፡ ከእነር ሱም ፡ ጋር ፡ ተቀምጠው ፡ የነበሩት ፡ ተነሡ ፥ ፴፩ ፈቀቅ ፡ ብለውም ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡— ይህ ፡ ሰው ፡ እንኳንስ ፡ ለሞት ፡ ለእስራትም ፡ የሚገባ ፡ ፴፪ ምንም ፡ አላደረገ ፡ ብለው ፡ ተነጋገሩ ። አግሪ ጳም ፡ ፊስጦስን ፡— ይህ ፡ ሰው ፡ እኮ ፡ ወደ ፡ ቄሣር ፡ ይግባኝ ፡ ባይል ፡ ይፈታ ፡ ዘንድ ፡ ይቻል ፡ ነበር ፡ አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፯ ።

፩ ወደ ፡ ኢጣሊያም ፡ በመርከብ ፡ እንሄድ ፡ ዘንድ ፡ በተቈረጠ ፡ ጊዜ ፥ ጳውሎስንና ፡ ሌሎችን ፡ እስ ረኞች ፡ ከአውግስጦስ ፡ ጭፍራ ፡ ለነበረ ፡ ዩል ዮስ ፡ ለሚሉት ፡ ለመቶ ፡ አለቃ ፡ አሳልፈው ፡ ፪ ሰጡአቸው ። በእስያም ፡ ዳርቻ ፡ ወዳሉ ፡ በፍ ራዎች ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ ባለው ፡ በአድራሚጢስ ፡ መርከብ ፡ ገብተን ፡ ተነሣን ፤ የመቄዶንያም ፡ ሰው ፡ የሆነ ፡ የተሰሎንቄው ፡ አርስጥርኮስ ፡ ከእኛ ፡ ፫ ጋር ፡ ነበረ ። በነገውም ፡ ወደ ፡ ሲዶና ፡ በገደ ርን ፡ ዩልዮስ ፡ ለጳውሎስ ፡ ቸርነት ፡ አድርጎ ፡ እርዳታቸውን ፡ ይቀበል ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ወዳ ፬ ጆቹ ፡ እንዲሄድ ፡ ፈቀደለት ። ከዚያም ፡ ተነ ሥተን ፡ ነፋሱ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ነበረና ፡ በቆጵ ፭ ሮስ ፡ ተተግነን ፡ ሄድን ፤ በኪልቅያና ፡ በጵንፍ ልያም አጠገብ ፡ ያለውን ፡ ባሕር ፡ ከተሻገርን ፡ በኋላ ፡ በሉቅያ ፡ወዳለ ፡ ወደ ፡ ሙራ ፡ ደረስን ። ፮ የመቶ ፡ አለቃውም ፡ በዚያ ፡ ወደ ፡ ኢጣሊያ ፡ የሚሄድ ፡ የእስክንድርያውን ፡ መርከብ ፡ አግ ፯ ኝቶ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አገባን ። ብዙ ፡ ቀንም ፡ እያ ዘገምን ፡ ሄደን ፡ በጭንቅ ፡ ወደ ፡ ቀኒዶስ ፡ አን ጻር ፡ ደረስን ፤ ነፋስም ፡ ስለ ፡ ከለከለን ፡ በቀርጤስ ፡ ፰ ተተግነን ፡ በሰልሙና ፡ አንጻር ፡ ሄድን ፤ በጭን ቅም ፡ ጥግ ፡ ጥጉን ፡ አልፈን ፡ ለላሲያ ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡ ቀረበች ፡ መልካም ፡ ወደብ ፡ ወደሚሉ ት ፡ ስፍራ ፡ መጣን ።

፱ ብዙ ፡ ጊዜም ፡ ካለፈ ፡ በኋላ ፥ የጦም ፡ ወራት ፡ አሁን ፡ አልፎ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ በመርከብ ፡ ለመሄድ ፡ ፲ አሁን ፡ የሚያስፈራ ፡ ነበርና ፡ ጳውሎስ ፡— እና ንተ ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡ ጒዞ ፡ በጥፋትና ፡ በብዙ ፡ ጒዳት ፡ እንዲሆን ፡ አያለሁ ፤ ጥፋቱም ፡ በገዛ ፡ ሕይወታችን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በጭነቱና ፡ በመር ከቡ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ ብሎ ፡ መከራቸው ። ፲፩ የመቶ ፡ አለቃው ፡ ግን ፡ ጳውሎስ ፡ ከተናገረው ፡ ይልቅ ፡ የመርከብ ፡ መሪውንና ፡ የመርከቡን ፡ ፲፪ ባለቤት ፡ ያምን ፡ ነበር ። ያም ፡ ወደብ ፡ ይከር ሙበት ፡ ዘንድ ፡ የማይመች ፡ ስለ ፡ ሆነ ፥ የሚበ ዙቱ ፡ ቢቻላቸው ፡ በሰሜንና ፡ በደቡብ ፡ ምዕ ራብ ፡ ትይዩ ፡ ወዳለው ፡ ፍንቄ ፡ ወደሚሉት ፡ ወደ ፡ ቀርጤስ ፡ ወደብ ፡ ደርሰው ፡ ይከርሙ ፡ ዘንድ ፡ ከዚያ ፡ እንዲነሡ ፡ መከሩ ።

፲፫ ልከኛም ፡ የደቡብ ፡ ነፋስ ፡ በነፈሰ ፡ ጊዜ ፥ አን ዳሰቡት ፡ የሆነላቸው ፡ መስሎአቸው ፡ ተነሡ ፡ በቀርጤስም ፡ አጠገብ ፡ ጥግ ፡ ጥጉን ፡ አለፉ ። ፲፬ ነገር ፡ ግን ፡ አጅግ ፡ ሳይዘገይ ፡ አውራቂስ ፡ የሚ ፲፭ ሉት ፡ ዓውሎ ፡ ነፋስ ፡ ከዚያ ፡ ወረደበቸው ፤ መር ከቡም ፡ ተነጥቆ ፡ ነፋሱን ፡ ሲቃወም ፡ መሄድ ፡ ፲፮ በላቻለ ፡ ለቀነው ፡ ተነዳን ። ቄዳ ፡ በሚሉአ ትም ፡ ደሴት ፡ በተተግንን ፡ ጊዜ ፡ ታንኳይቱን ፡ ፲፯ ለመግዛት ፡ በጭንቅ ፡ ቻልን ፤ ወደ ፡ ላይም ፡ ካወጡአት ፡ በኋላ ፡ መርከቡን ፡ በገመድ ፡ አስታ ጥቀው ፡ አጸኑ ፤ ስርቲስም ፡ ወደሚሉት ፡ ወደ ፡ አሸዋ ፡ እንዳይወድቁ ፡ ፈርተው ፡ ሸራውን ፡ ፲፰ አውርደው ፡ እንዲሁ ፡ ተነዱ ። ነፋሱም ፡ በር ትቶ ፡ ሲያስጨንቀን ፡ በማግሥቱ ፡ ከጭነቱ ፡ ፲፱ ወደ ፡ ባሕር ፡ ይጥሉ ፡ ነበር ፥ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ የመርከቡን ፡ ዕቃ ፡ በእጃችን ፡ ወረወርን ። ፳ ብዙ ፡ ቀንም ፡ ፀሐይን ፡ ከዋክብትንም ፡ ሳናይ ፡ ትልቅ ፡ ነፋስም ፡ ሲበረታብን ፡ ጊዜ ፥ ወደ ፡ ፊት ፡ እንድናለን ፡ የማለት ፡ ተስፋ ፡ ሁሉ ፡ ተቈረጠ ።

፳፩ ሳይበሉም ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ ከቆዩ ፡ በኋላ ፥ ያን ፡ ጊዜ ፡ ጳውሎስ ፡ በመካከላቸው ፡ ቆሞ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ፥ ሰምታችሁኝ ፡ በሆነ ፡ ኖሮ ፡ ከቀርጤስ ፡ እንዳትነሡ ፡ ይህንም ፡ ጥፋትና ፡ ጒዳት ፡ እንዳታገኙ ፡ ይገባችሁ ፡ ነበር ። ፳፪ አሁንም ፡— አይዞአችሁ ፡ ብዬ ፡ እመክራችኋ ለሁ ፤ ይህ ፡ መርከብ ፡ እንጂ ፡ ከእናንተ ፡ አንድ ፡ ፳፫ ነፍስ ፡ እንኳ ፡ አይጠፋምና ። የእርሱ ፡ የምሆ ንና ፡ ደግሞ ፡ የማመልከው ፡ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ በዚች ፡ ሌሊት ፡ በአጠገቤ ፡ ቆሞ ፡ ፳፬ ነበርና ፥ እርሱም ፡— ጳውሎስ ፡ ሆይ ፥ አትፍራ ፤ በቄሣር ፡ ፊት ፡ ልትቆም ፡ ይገባሃል ፤ እነሆም ፥ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ የሚሄዱትን ፡ ፳፭ ሁሉ ፡ ሰጥቶሃል ፡ አለኝ ። ስለዚህም ፡ እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ፥ አይዞአችሁ ፤ እንደ ፡ ተናገረኝ ፡ እንዲሁ ፡ እንዲሆን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አምናለ ሁና ። ፳፮ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ አንዲት ፡ ደሴት ፡ እን

፳፮። ፳፮፤ ዮሐ· ፲፰ ፥ ፳ ። ፴፪፤ ም· ፳፭ ፥ ፲፩ ።
፳፯። ፪፤ ም· ፲፱ ፥ ፳፱ ። ፱፤ ዘሌዋ· ፲፮ ፥ ፳፱ ። ፳፪፤ ም· ፭ ፥ ፲፱ ። ፳፫፤ ም· ፳፫ ፥ ፲፩ ።

ድንወድቅ ፡ ያስፈልገናል ።
፳፯ በአሥራ ፡ አራተኛውም ፡ ሌሊት ፡ በአድርያ ፡ ባሕር ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ ስንነዳ ÷ መርከበኞች ፡ በእኩለ ፡ ሌሊት ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ ምድር ፡ የቀ
፳፰ ረቡ ፡ መሰላቸው ። መለኪያ ፡ ገመድም ፡ ቢጥሉ ፡ ሀያ ፡ በሰው ፡ ቁመት ፡ አገኙ ፡ ጥቂትም ፡ ቆይተው ፡ ሁለተኛ ፡ ቢጥሉ ፡ አሥራ ፡ አምስት ፡ በሰው ፡
፳፱ ቁመት ፡ አገኙ ፤ ድንጋያማም ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ስፍራ ፡ እንዳይወድቁ ፡ ፈርተው ÷ ከመርከቡ ፡ በስተ ፡ ኋላ ፡ አራት ፡ መልሕቅ ፡ አወረዱ ÷ ቀንም ፡ እን
፴ ዲሆን ፡ ተመኙ ። መርከበኞቹም ፡ ከመርከቡ ፡ ይሸሹ ፡ ዘንድ ፡ ፈልገው ፡ ከመርከቡ ፡ በስተ ፡ ፊት ፡ መልሕቅ ፡ መጣል ፡ እንዳላቸው ፡ አመከ ኙተው ፡ ታንኳይቱን ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ባወረዱ ፡
፴፩ ጊዜ ÷ ጳውሎስ ፡ ለመቶ ፡ አለቃውና ፡ ለወታደ ሮች ፡— እነዚህ ፡ በመርከቡ ፡ ካልቆዩ ፡ እናንተ ፡
፴፪ ትድኑ ፡ ዘንድ ፡ አትችሉም ፡ አላቸው ። ያን ፡ ጊዜ ፡ ወታደሮቹ ፡ የታንኳይቱን ፡ ገመድ ፡ ቈር ጠው ፡ ትወድቅ ፡ ዘንድ ፡ ተዉአት ።
፴፫ ቀንም ፡ ቢነጋ ፡ ጳውሎስ ፡ ምግብ ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ ሁሉን ፡ ይለምን ፡ ነበር ÷ እንዲህም ፡ አላ ቸው ፡— እየጠበቃችሁ ፡ ምንም ፡ ሳትቀበሉ ፡ ጦማችሁን ፡ ከሰነበታችሁ ፡ ዛሬ ፡ አሥራ ፡ አራ
፴፬ ተኛ ፡ ቀናችሁ ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ ምግብ ፡ ትበሉ ፡ ዘንድ ፡ እለምናችኋለሁ ፤ ይህ ፡ ለደኅንነታችሁ ፡ ይሆናልና ፤ ከእናንተ ፡ ከአንዱ ፡ የራስ ፡ ጠጕር ፡
፴፭ እንኳ ፡ አትጠፋምና ። ይህንም ፡ ብሎ ፡ እንጀ ራን ፡ ይዞ ፡ በሁሉ ፡ ፊት ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመ
፴፮ ሰገነ ፡ ቈርሶም ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ ጀመረ ። ሁሉም ፡ ተጽናንተው ፡ ራሳቸው ፡ ደግሞ ፡ ምግብ ፡ ተቀ
፴፯ በሉ ። በመርከቡም ፡ ያለን ፡ ሁላችን ፡ ሁለት ፡
፴፰ መቶ ፡ ሰባ ፡ ስድስት ፡ ነፍስ ፡ ነበርን ። በልተ ውም ፡ በጠገቡ ፡ ጊዜ ፡ ስንዴውን ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ እየጣሉ ፡ መርከቡን ፡ አቃለሉት ።
፴፱ በነጋም ፡ ጊዜ ፡ ምድሩን ፡ አላወቁትም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ የአሸዋ ፡ ዳር ፡ ያለውን ፡ የባሕር ፡ ሰርጥ ፡ ተመለከቱ ÷ ቢቻላቸውም ፡ መርከቡን ፡ ወደዚያ ፡
፵ ይገፉ ፡ ዘንድ ፡ ቈረጡ ። መልሕቆቹንም ፡ ፈት ተው ፡ በባሕር ፡ ተዉአቸው ÷ ያን ፡ ጊዜም ፡ የመቅዘፊያውን ፡ ማሠሪያ ፡ ፈቱት ፤ ታናሹንም ፡ ሸራ ፡ ለነፋስ ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡ ወደ ፡ ዳር ፡ አቅ
፵፩ ንተው ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ጀመሩ ። ነገር ፡ ግን ፡ ሁለት ፡ ባሕር ፡ በተገናኙበት ፡ ስፍራ ፡ ወድቀው ፡ መርከቡን ፡ በዲብ ፡ ላይ ፡ ነዱ ፤ በስተ ፡ ፊቱም ፡ ተተክሎ ፡ የማይነቃነቅ ፡ ሆነ ÷ በስተ ፡ ኋላው ፡ ግን ፡ ከማዕበሉ ፡ ግፊያ ፡ የተነሣ ፡ ይሰበር ፡ ነበር ።
፵፪ ወታደሮቹም ፡ ከእስረኞች ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ ዋኝቶ ፡ እንዳያመልጥ ፡ ይገድሉአቸው ፡ ዘንድ ፡ ተማ
፵፫ ከሩ ። የመቶ ፡ አለቃው ፡ ግን ፡ ጳውሎስን ፡ ያድ ነው ፡ ዘንድ ፡ አስቦ ፡ ምክራቸውን ፡ ከለከለ ፤ ዋና ፡ የሚያውቁትም ፡ ከመርከብ ፡ ራሳቸውን ፡ እየወረወሩ ፡ አስቀድመው ፡ ወደ ፡ ምድር ፡
፵፬ ይወጡ ፡ ዘንድ ÷ የቀሩትም ፡ አንዳንዱ ፡ በሳን ቃዎች ፡ ላይ ፡ እንዳንዱም ፡ በመርከቡ ፡ ስባሪ ፡ ይወጡ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ። እንዲሁም ፡ ሁሉ ፡ በደ ኅና ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ደረሱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

፩ በደኅና ፡ ከደረስን ፡ በኋላ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ደሴቲቱ ፡ መላጥያ ፡ እንድትባል ፡ አወቅን ።
፪ አረማውያንም ፡ የሚያስገርም ፡ ቸርነት ፡ አደረ ጉልን ፤ ዝናብ ፡ ስለ ፡ ሆነም ፡ ስለ ፡ ብርዱም ፡
፫ እሳት ፡ አንድደው ፡ ሁላችንን ፡ ተቀበሉን ። ጳው ሎስ ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ጭራሮ ፡ አከማችቶ ፡ ወደ ፡ እሳት ፡ ሲጨምር ፡ እፉኝት ፡ ከሙቀት ፡ የተነሣ ፡
፬ ወጥታ ፡ እጁን ፡ ነደፈችው ። አረማውያንም ፡ አባብ ፡ በእጁ ፡ ተንጠልጥላ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ÷ እርስ ፡ በርሳቸው ፡— ይህ ፡ ሰው ፡ በእርግጥ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ነው ÷ ከባሕርም ፡ ስንኳ ፡ በደኅና ፡ ቢወጣ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ በሕይወት ፡ ይኖር ፡
፭ ዘንድ ፡ አልተወውም ፡ አሉ ። እርሱ ፡ ግን ፡ እባቢቱን ፡ ወደ ፡ እሳት ፡ አራገፋት ፡ አንዳችም ፡
፮ አልጐዳችውም ፤ እነርሱም ፡— ሊያብጥ ፡ ወይም ፡ ወዲያው ፡ ሞቶ ፡ ሊወድቅ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ይጠባበቁት ፡ ነበር ። ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ሲጠባበቁ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ የሚያስገርም ፡ ነገር ፡ ምንም ፡ ባላዩ ፡ ጊዜ ፡— ይህስ ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ አሳባቸውን ፡ ለወጡ ።
፯ በዚያም ፡ ስፍራ ፡ አጠገብ ፡ ፑፕልዮስ ፡ የሚ ሉት ፡ የደሴት ፡ አለቃ ፡ መሬት ፡ ነበረ ÷ እርሱም ፡ እንግድነት ፡ ተቀብሉን ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ በፍቅር ፡
፰ አሳደረን ። የፑፕልዮስም ፡ አባት ፡ በንዳድና ፡ በተቅማጥ ፡ ታሞ ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ፤ ጳውሎስም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ገብቶ ፡ ጸለየለት ፡ እጁንም ፡ በላዩ ፡
፱ ጭኖ ፡ ፈወሰው ። ይህም ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ የቀ ሩት ፡ ደግሞ ፡ በደሴቲቱ ፡ ደዌ ፡ የነበረባቸው ፡
፲ እየመጡ ፡ ተፈወሱ ፤ በብዙ ፡ ክብርም ፡ ደግሞ ፡ አከበሩን ÷ በተነሣንም ፡ ጊዜ ፡ በመርከብ ፡ ላይ ፡ የሚያስፈልገንን ፡ ነገር ፡ አኖሩልን ።
፲፩ ከሦስት ፡ ወርም ፡ በኋላ ፡ በደሴቲቱ ፡ ከርሞ ፡ በነበረው ፡ በእስክንድርያው ፡ መርከብ ፡ ተነሣን ÷ በእርሱም ፡ የዲዮስቆሮስ ፡ አላማ ፡ ነበረበት ።
፲፪ ወደ ፡ ሰራኩስም ፡ በገባን ፡ ጊዜ ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡
፲፫ ተቀመጥን ፤ ከዚያም ፡ እየተዛወርን ፡ ወደ ፡ ሬጊ ዮም ፡ ደረስን ። ከአንድ ፡ ቀን ፡ በኋላም ፡ የደ ቡብ ፡ ነፋስ ፡ በነፈሰ ፡ ጊዜ ፡ በሁለተኛው ፡ ቀን ፡
፲፬ ወደ ፡ ፑቲዮሉስ ፡ መጣን ። በዚያም ፡ ወንድሞ ችን ፡ አግኝተን ፡ በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ እንድንቀመጥ ፡ ለመኑን ፤ እንዲሁም ፡ ወደ ፡
፲፭ ሮሜ ፡ መጣን ። ከዚያም ፡ ወንድሞች ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ ሰምተው ፡ እስከ ፡ አፍዩስ ፡ ፋሩስና ፡ ሦስት ፡ ማደሪያ ፡ እስከሚባለው ፡ ሊቀበሉን ፡ ወጡ ÷ ጳውሎስም ፡ ባያቸው ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡

፳፯። ፴፬፤ ማቴ ፲÷፴። ፴፭፤ ማቴ ፲፭÷፴፮።
፳፰። ፭፤ ማር ፲፮÷፲፰። ፰፤ ም ፲፱÷፲፩።

አመሰገነ ፡ ልቡም ፡ ተጽናና ። ፲፮ ወደ ፡ ሮሜም ፡ በገባን ፡ ጊዜ ፡ ጳውሎስ ፡ ከሚጠብቀው ፡ ወታደር ፡ ጋር ፡ ለብቻው ፡ ይቀመጥ ፡ ዘንድ ፡ ተፈቀደለት ።

፲፯ ከሦስት ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ጳውሎስ ፡ የአይሁድን ፡ ታላላቆች ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ጠራ ፤ በተሰበሰቡም ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡— ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ እኔ ፡ ሕዝቡን ፡ ወይም ፡ የአበቶችን ፡ ሥርዓት ፡ የሚቃወም ፡ አንዳች ፡ ሳላደርግ ፥ ከኢየሩሳሌም ፡ እንደ ፡ ታሰርሁ ፡ በሮማውያን ፡ እጅ ፡ ፲፰ አሳልፈው ፡ ሰጡኝ ። እነርሱም ፡ መርምረው ፡ ለሞት ፡ የሚገባ ፡ ምክንያት ፡ ስላልነበረብኝ ፡ ፲፱ ሊፈቱኝ ፡ አሰቡ ፤ አይሁድ ፡ ግን ፡ በተቃወሙ ፡ ጊዜ ፥ ወደ ፡ ቄሣር ፡ ይግባኝ ፡ እንድል ፡ ግድ ፡ ሆነብኝ ፡ እንጂ ፡ ሕዝቤን ፡ የምከስበት ፡ ነገር ፡ ፳ ኖሮኝ ፡ አይደለም ። ስለዚህም ፡ ምክንያት ፡ እያችሁና ፡ እንግራችሁ ፡ ዘንድ ፡ ጠራኋችሁ ፤ ስለ ፡ እስራኤል ፡ ተስፋ ፡ ይህን ፡ ሰንሰለት ፡ ለብ ፡ ፳፩ ሻለሁና ። እነርሱም ፡— እኛ ፡ ከይሁዳ ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ ደብዳቤ ፡ አልተቀበልንም ፥ ከወንድሞችም ፡ አንድ ፡ ሰንኳ ፡ መጥቶ ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አላወራልንም ፡ ወይም ፡ አልተናገረብ ፡ ፳፪ ህም ። ነገር ፡ ግን ፡ ስለዚህ ፡ ወገን ፡ በየስፍራው ፡ ሁሉ ፡ እንዲቃወሙ ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ ታውቆአልና ፡ የምታስበውን ፡ ከአንተ ፡ እንሰማ ፡ ዘንድ ፡ እንፈቅዳለን ፡ አሉት ።

፳፫ ቀንም ፡ ቀጥረውለት ፡ ብዙ ፡ ሆነው ፡ ወደ ፡ መኖሪያው ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ መጡ ፤ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥትም ፡ እየመሰከረ ፡ ስለ ፡ ኢየሱስም ፡ ከሙሴ ፡ ሕግና ፡ ከነቢያት ፡ ጠቅሶ ፡ እያስረዳቸው ፥ ከጥዋት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ ይገልጥላቸው ፡ ነበር ። ፳፬ እኵሌቶቹም ፡ የተናገረውን ፡ አመኑ ፥ እኵሌቶቹ ፡ ግን ፡ አላመኑም ፤ ፳፭ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ በልተስማሙ ፡ ጊዜ ፥ ጳውሎስ ፡ አንዲት ፡ ቃል ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ ሄዱ ፤ እንዲህም ፡ አለ ፡— መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በነቢዩ ፡ በኢሳይያስ ፡ ለአበቶቻችን ፡—

፳፮ ወደዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ሂድና ፡— መስማትን ፡ ትሰማላችሁና ፡ አታስተውሉም ፥ ማየትንም ፡ ታያላችሁና ፡ አትመለከቱም ፤ ፳፯ በዓይናቸው ፡ እንዳያዩ ፡ በጆሮአቸውም ፡ እንዳይሰሙ ፡ በልባቸውም ፡ እንዳያስተውሉ ፡ ተመልሰውም ፡ እንዳልፈውሳቸው ፥ የዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ልብ ፡ ደንድኖአል ፡ ጆሮአቸውም ፡ ደንቁሮአል ፡ ዓይናቸውንም ፡ ጨፍነዋል ፡ በላቸው ፡

ሲል ፡ መልካም ፡ ተናገረ ። ፳፰ እንግዲህ ፡ ይህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማዳን ፡ ለአሕዛብ ፡ እንደ ፡ ተላከ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ የታወቀ ፡ ይሁን ፤ እነርሱ ፡ ደግሞ ፡ ይሰሙታል ። ፳፱ ይህንም ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ፡ አይሁድ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ እጅግ ፡ እየተከራከሩ ፡ ሄዱ ።

፴ ጳውሎስም ፡ በተከራየው ፡ ቤት ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ሙሉ ፡ ተቀመጠ ፥ ወደ ፡ እርሱም ፡ የሚመጡትን ፡ ሁሉ ፡ ይቀበል ፡ ነበር ፤ ፴፩ ማንም ፡ ሳይከለክለው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ እየሰበከ ፡ ስለ ፡ ጌታ ፡ ስለ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እጅግ ፡ ገልጦ ፡ ያስተምር ፡ ነበር ።

# የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ሮሜ ፡ ሰዎች ።

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ ሐዋርያ ፡ ሊሆን ፡ የተጠራ ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ባሪያ ፡ ጳውሎስ ፡ በነቢያቱ ፡ አፍ ፡ በቅዱሳን ፡ መጻሕፍት ፡ አስቀድሞ ፡ ተስፋ ፡ ለሰጠው ፡ ፪ ለእግዚአብሔር ፡ ወንጌል ፡ ተለየ ። ይህም ፡ ወንጌል ፡ በሥጋ ፡ ከዳዊት ፡ ዘር ፡ ስለ ፡ ተወለደ ፡ እንደ ፡ ቅድስና ፡ መንፈስ ፡ ግን ፡ ከሙታን ፡ መነሣት ፡ የተነሣ ፡ በኃይል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ሆኖ ፡ ስለ ፡ ተገለጠ ፡ ስለ ፡ ልጁ ፡ ነው ፤ እርሱም ፡ ፬ ጌታችን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ነው ። በእርሱም ፡ ስለ ፡ ስሙ ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ ከእምነት ፡ የሚነሣ ፡ መታዘዝ ፡ እንዲገኝ ፡ ጸጋ ፡ ፭ ንና ፡ ሐዋርያነትን ፡ ተቀበልን ፤ በእነርሱም ፡ መካከል ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ልትሆኑ ፡ የተጠራችሁ ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ናችሁ ። ፯ በእግዚአብሔር ፡ ለተወደዳችሁና ፡ ቅዱሳን ፡ ልትሆኑ ፡ ለተጠራችሁ ፡ በሮሜ ፡ ላላችሁት ፡ ሁሉ ፥ ከእግዚአብሔር ፡ ከአባታችን ፡ ከጌታም ፡ ከኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋና ፡ ሰላም ፡ ለእናንተ ፡ ይሁን ።

፰ እምነታችሁ ፡ በዓለም ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ተሰማች ፡ አስቀድሜ ፡ ስለ ፡ ሁላችሁ ፡ አምላኬን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አመሰግናለሁ ። ፱ በልጁ ፡ ወንጌል ፡ በመንፈሴ ፡ የማገለግለው ፡ እግዚአብሔር ፡ ምስክሬ ፡ ነውና ፤ ምናልባት ፡ ብዙ ፡ ቆይቼ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ አሁን ፡ እንድመጣ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ መንገዴን ፡ እንዲያቀናልኝ ፡ እየለመንሁ ፡ ሁልጊዜ ፡ ስጸልይ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ሳላ

፳፰ ። ፲፯ ፤ ምዕ ፳፭ ፥ ፰ ። ፲፰ ፤ ምዕ ፳፫ ፥ ፳፱ ፤ ፳፮ ፥ ፴፪ ። ፲፱ ፤ ምዕ ፳፭ ፥ ፲፩ ። ፳ ፤ ምዕ ፳፮ ፥ ፯ ፡ ፮ ። ፳፮ ፡ ፳፯ ፤ ኢሳ ፮ ፥ ፱ ፡ ፲ ።

፩ ። ፩ ፤ የሐዋ ፱ ፥ ፲፭ ፤ ፲፫ ፥ ፪ ። ፫ ፤ ማቴ ፩ ፥ ፩—፲፯ ። ፬ ፤ የሐዋ ፲፫ ፥ ፴፫ ። ፭ ፤ ገላ ፩ ፥ ፲፭ ፡ ፲፮ ። ፱ ፤ ፪ ጢሞ ፩ ፥ ፫ ። ፲ ፤ ምዕ ፲፭ ፥ ፳፱ ፡ ፴፪ ፤ የሐዋ ፲፱ ፥ ፳፩ ።

፲፩ ቋርጥ ፡ አሳስባለሁ ። ትጸኑ ፡ ዘንድ ፡ መንፈሳዊ ፡ ስጦታ ፡ እንዳካፍላችሁ ፡ ላያችሁ ፡ እናፍቃለ
፲፪ ሁና ፤ ይህንም ፡ ማለቴ ፡ በመካከላችን ፡ ባለች ፡ በእናንተና ፡ በእኔ ፡ እምነት ፡ አብረን ፡ በእናንተ ፡
፲፫ እንድንጽናና ፡ ነው ። ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ በሌ ሎቹ ፡ አሕዛብ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በእናንተም ፡ ፍሬ ፡ አገኝ ፡ ዘንድ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ልመጣ ፡ እንዳሰብሁ ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ ግን ፡ እንደ ፡
፲፬ ተከለከልሁ ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ እወዳለሁ ። ለግ ሪክ ፡ ሰዎችና ፡ ላልተማሩም ፥ ለጥበበኞችና ፡
፲፭ ለማያስተውሉም ፡ ዕዳ ፡ አለብኝ ፤ ስለዚህም ፡ በሚቻለኝ ፡ መጠን ፡ በሮሜ ፡ ላላችሁ ፡ ለእና ንተ ፡ ደግሞ ፡ ወንጌልን ፡ ልሰብክ ፡ ተዘጋጅቼ አለሁ ።

፲፮ በወንጌል ፡ አላፍርምና ፤ አስቀድሞ ፡ ለአይሁ ዳዊ ፡ ደግሞም ፡ ለግሪክ ፡ ሰው ፥ ለሚያምኑ ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ኃይል ፡ ለማዳን ፡ ነውና ።
፲፯ ጻድቅ ፡ በእምነት ፡ ይኖራል ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጽድቅ ፡ ከእምነት ፡ ወደ ፡ እምነት ፡ በእርሱ ፡ ይገለጣልና ።

፲፰ እውነትን ፡ በዓመፃ ፡ በሚከለክሉ ፡ ሰዎች ፡ በኃ ጢአተኝነታቸውና ፡ በዓመፃቸው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ ከሰማይ ፡ ይገለጣልና ፤
፲፱ እግዚአብሔር ፡ ለእ ፡ ገለጠላቸው ፥ ስለ ፡ እግዚ አብሔር ፡ ሊታወቅ ፡ የሚቻለው ፡ በእነርሱ ፡
፳ ዘንድ ፡ ግልጥ ፡ ነውና ። የማይታየው ፡ ባሕርይ ፡ እርሱም ፡ የዘላለም ፡ ኃይሉ ፡ ደግሞም ፡ አምላ ክነቱ ፡ ከዓለም ፡ ፍጥረት ፡ ጀምሮ ፡ ከተሠሩት ፡ ታውቆ ፡ ግልጥ ፡ ሆኖ ፡ ይታያልና ፤ ስለዚህም ፡ እግዚአብሔርን ፡ እያወቁ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔ ርነቱ ፡ መጠን ፡ ስላላከበሩትና ፡ ስላላመሰገኑት ፡ የሚያመካኙት ፡ አጡ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በአሳባቸው ፡ ከንቱ ፡ ሆኑ ፡ የማያስተውለውም ፡ ልባቸው ፡
፳፪ ጨለመ ። ጥበበኞች ፡ ነን ፡ ሲሉ ፡ ደንቆሮ ፡ ሆኑ ፥
፳፫ የማይጠፋውንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ክብር ፡ በሚጠፋ ፡ ሰውና ፡ በወፎች ፡ አራት ፡ እግር ፡ ባላቸውም ፡ በሚንቀሳቀሱትም ፡ መልክ ፡ መሰ ለው ፡ ለወጡ ።

፳፬ ስለዚህ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ሥጋቸውን ፡ ሊያ ዋርዱ ፡ እግዚአብሔር ፡ በልባቸው ፡ ፍትወት ፡
፳፭ ወደ ፡ ርኩሰት ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፤ ይህም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ እውነት ፡ በውሸት ፡ ስለ ፡ ለወጡ ፡ በፈጣሪም ፡ ፈንታ ፡ የተፈጠረውን ፡ ስላ መለኩና ፡ ስላገለገሉ ፡ ነው ፤ እርሱም ፡ ለዘላለም ፡ የተባረከ ፡ ነው ፤ አሜን ።

፳፮ ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሚያስነውር ፡ ምኞት ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፤ ሴቶቻቸውም ፡ ለባ ሕርያቸው ፡ የሚገባውን ፡ ሥራ ፡ ለባሕርያቸው ፡
፳፯ ለማይገባው ፡ ለወጡ ፤ እንዲሁም ፡ ወንዶች ፡ ደግሞ ፡ ለባሕርያቸው ፡ የሚገባውን ፡ ሴቶችን ፡ መገናኘት ፡ ትተው ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ በፍት ወታቸው ፡ ተቃጠሉ ፤ ወንዶችም ፡ በወንዶች ፡ ነውር ፡ አድርገው ፡ በስሕተታቸው ፡ የሚገባ ውን ፡ ብድራት ፡ በራሳቸው ፡ ተቀበሉ ።

፳፰ እግዚአብሔርን ፡ ለማወቅ ፡ ባልወደዱት ፡ መጠን ፡ እግዚአብሔር ፡ የማይገባውን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ለማይረባ ፡ አእምሮ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፤
፳፱ ዓመፃ ፡ ሁሉ ፥ ግፍ ፥ መመኘት ፥ ክፋት ፡ ሞላባ ቸው ፤ ቅናትን ፥ ነፍስ ፡ መግደልን ፥ ክርክርን ፥ ተንኰልን ፥ ክፉ ፡ ጠባይን ፡ ተሞሉ ፤ የሚያሾ
፴ ከሹኩ ፥ ሐሜተኞች ፥ አምላክን ፡ የሚጠሉ ፥ የሚያንገላቱ ፥ ትዕቢተኞች ፥ ትምክህተኞች ፥ ክፋትን ፡ የሚፈላለጉ ፥ ለወላጆቻቸው ፡ የማይ
፴፩ ታዘዙ ፥ የማያስተውሉ ፥ ውል ፡ የሚያፈርሱ ፥ ፍቅር ፡ የሌላቸው ፥ ምሕረት ፡ ያጡ ፡ ናቸው ፤
፴፪ እንደነዚህ ፡ ለሚያደርጉት ፡ ሞት ፡ ይገባቸዋል ፡ የሚለውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ እያወቁ ፡ እነዚህን ፡ ከሚያደርጉ ፡ ጋር ፡ ይስማማሉ ፡ እንጂ ፡ አድራጊዎች ፡ ብቻ ፡ አይደሉም ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ስለዚህ ፥ አንተ ፡ የምትፈርድ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሆይ ፥ የምታመካኘው ፡ የለህም ፤ በሌላው ፡ በም ትፈርድበት ፡ ነገር ፡ ራስህን ፡ ትኰንናለህና ፤ አንተው ፡ ፈራጁ ፡ እነዚያን ፡ ታደርጋለህና ።
፪ እንደዚህም ፡ በሚያደርጉት ፡ ላይ ፡ የእግዚአብ ሔር ፡ ፍርድ ፡ እውነተኛ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እናው
፫ ቃለን ። አንተም ፡ እንደዚህ ፡ በሚያደርጉ ፡ የም ትፈርድ ፡ ያንም ፡ የምታደርግ ፡ ሰው ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ የምታመልጥ ፡
፬ ይመስልሃልን ? ወይስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቸር ነት ፡ ወደ ፡ ንስሐ ፡ እንዲመራህ ፡ ሳታውቅ ፡ የቸ ርነቱንና ፡ የመቻሉን ፡ የትዕግሥቱንም ፡ ባለ ፡
፭ ጠግነት ፡ ትንቃለህን ? ነገር ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ጥንካ ሬህና ፡ ንስሐ ፡ እንደማይገባ ፡ ልብህ ፡ የእግዚ አብሔር ፡ ቅን ፡ ፍርድ ፡ በሚገለጥበት ፡ በቍጣ ፡ ቀን ፡ ቍጣን ፡ በራስህ ፡ ላይ ፡ ታከማቻለህ ።
፮ እርሱ ፡ ለእያንዳንዱ ፡ እንደ ፡ ሥራው ፡ ያስረክ
፯ በዋል ፤ በበጎ ፡ ሥራ ፡ በመጽናት ፡ ምስጋናንና ፡ ክብርን ፡ የማይጠፋንም ፡ ሕይወት ፡ ለሚፈልጉ ፡
፰ የዘላለምን ፡ ሕይወት ፡ ይሰጣቸዋል ፤ ለዓመፃ ፡ ለሚታዘዙ ፡ እንጂ ፡ ለእውነት ፡ ለማይታዘዙ ትና ፡ ለአድመኞች ፡ ላይ ፡ ግን ፡ ቍጣና ፡ መቅ
፱ ሠፍት ፡ ይሆንባቸዋል ። ክፉውን ፡ በሚያደ ርግ ፡ ሰው ፡ ነፍስ ፡ ሁሉ ፡ መከራና ፡ ጭንቀት ፡ ይሆንበታል ፥ አስቀድሞ ፡ ለአይሁዳዊ ፡ ደግ
፲ ሞም ፡ ለግሪክ ፡ ሰው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ለሚያደርጉ ፡ ሁሉ ፡ ምስጋናና ፡ ክብር ፡ ሰላምም ፡

፩። ፲፰፤ ፩ ቆሮ. ፩ ፥ ፳፩ ፡ ፳፬ ። ፲፯፤ ም. ፫ ፥ ፳፩ ፡ ፳፪ ፤ እንባ. ፪ ፥ ፬ ። ፲፱፤ የሐዋ. ፲፬ ፥ ፲፯ ። ፳፤ መዝ. ፲፱ ፥ ፩—፫ ። ፳፩፤ ኤፌ. ፬ ፥ ፲፯ ፡ ፲፰ ። ፳፪፤ ኤር. ፲ ፥ ፲፬ ፤ ፩ ቆሮ. ፩ ፥ ፳ ። ፳፫፤ ዘዳግ. ፬ ፥ ፲፭—፲፰ ፤ መዝ. ፻፮ ፥ ፳ ። ፳፬፤ መዝ. ፹፩ ፥ ፲፪ ። ፳፯፤ ዘሌዋ. ፲፰ ፥ ፳፪ ። ፴፪፤ ሆሴ. ፯ ፥ ፩—፫ ።
፪። ፩፤ ማቴ. ፯ ፥ ፩ ፡ ፪ ። ፬፤ ዘፀአ. ፴፬ ፥ ፮ ፤ ፪ ጴጥ. ፫ ፥ ፱ ፡ ፲፭ ። ፮፤ ኢዮ. ፴፬ ፥ ፲፩ ፡ ፲፪ ። ፯፤ መዝ. ፷፪ ፥ ፲፪ ፤ ምሳ. ፳፬ ፥ ፲፪ ፤ ማቴ. ፲፮ ፥ ፳፯ ።

ይሆንላቸዋል ÷ አስቀድሞ ፡ ለአይሁዳዊ ፡ ደግ
፲፩ ሞም፡ ለግሪክ ፡ ሰው ። እግዚአብሔር፡ ለሰው፡
ፊት ፡ አያደላምና ።
፲፪ ያለ ፡ ሕግ ፡ ኀጢአት ፡ ያደረጉ ፡ ሁሉ ፡ ያለ ፡
ሕግ ፡ ደግሞ ፡ ይጠፋሉና ፤ ሕግም ፡ ሳላቸው ፡
ኀጢአት ፡ ያደረጉ ፡ ሁሉ ፡ በሕግ ፡ ይፈረድባቸ
፲፫ ዋል ፤ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሕግን ፡ የሚያ
ደርጉት ፡ ይጸድቃሉ ፡ እንጂ ፡ ሕግን ፡ የሚሰሙ ፡
፲፬ ጻድቃን ፡ አይደሉምና ። ሕግ ፡ የሌላቸው ፡ አሕ
ዛብ ፡ ከባሕርያቸው ፡ የሕግን ፡ ትእዛዝ ፡ ሲያደ
ርጉ ÷ እነዚያ ፡ ሕግ ፡ በይኖራቸው ፡ እንኳ ፡ ለራ
፲፭ ሳቸው ፡ ሕግ ፡ ናቸውና ፤ እነርሱም ፡ ሕሊና
ቸው ፡ ሲመሰክርላቸው ÷ አሳባቸውም ፡ እርስ ፡
በርሳቸው ፡ ሲከሰስ ፡ ወይም ፡ ሲያመካኝ ፡ በል
ባቸው ፡ የተጻፈውን ፡ የሕግ ፡ ሥራ ፡ ያሳያሉ ።
፲፮ ይህም ፡ እግዚአብሔር ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡
እኔ ፡ በወንጌል ፡ እንዳስተማርሁ ፡ በሰው ፡ ዘንድ ፡
የተሰወረውን ፡ በሚፈርድበት ፡ ቀን ፡ ይሆናል ።
፲፯ አንተ ፡ ግን ፡ አይሁዳዊ ፡ ብትባል ፡ በሕግም ፡
፲፰ ብትደገፍ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ብትመካ ÷ ፈቃ
ዱንም ፡ ብታውቅ ፡ ከሕግም ፡ ተምረህ ፡ የሚሻ
፲፱፡፳ ለውን ፡ ፈትነህ ፡ ብትወድ ፤ በሕግም ፡ የእውቀ
ትና ፡ የእውነት ፡ መልክ ፡ ስላለህ ÷ የዕውሮች ፡
መሪ ÷ በጨለማም ፡ ላሉ ፡ ብርሃን ÷ የሰነፎችም ፡
አስተማሪ ÷ የሕፃናትም ፡ መምህር ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡
፳፩ በራስህ ፡ ብትታመን ፤ እንግዲህ ፡ አንተ ፡ ሌላ
ውን ፡ የምታስተምር ፡ ራስህን ፡ አታስተምር
ምን ? አትስረቅ ፡ ብለህ ፡ የምትሰብክ ፡ ትሰርቃ
፳፪ ለህን ? አታመንዝር ፡ የምትል ፡ ታመነዝራለ
ህን ? ጣዖትን ፡ የምትጸየፍ ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡
፳፫ ትዘርፋለህን ? በሕግ ፡ የምትመካ ፡ ሕግን ፡ በመ
፳፬ ተላለፍ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ታሳፍራለህን ? በአ
ናንተ ፡ ሰበብ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ በአሕዛብ ፡
መካከል ፡ ይሰደባልና ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ።
፳፭ ሕግን ፡ ብታደርግ ፡ መገረዝስ ፡ ይጠቅማል ፤
ሕግን ፡ ተላላፊ ፡ ብትሆን ፡ ግን ፡ መገረዝህ ፡ አለ
፳፮ መገረዝ ፡ ሆኖአል ። እንግዲህ ፡ ያልተገረዘ ፡
ሰው ፡ የሕግን ፡ ሥርዓት ፡ ቢጠብቅ ፡ አለመገረዙ ፡
፳፯ እንደ ፡ መገረዝ ፡ ሆኖ ፡ አይቈጠርለትምን ? ከፍ
ጥረቱም ፡ ያልተገረዘ ፡ ሕግን ፡ የሚፈጽም ፡ ሰው ፡
የሕግ ፡ መጽሐፍና ፡ መገረዝ ፡ ሳለህ ፡ ሕግን ፡
፳፰ በምትተላለፈው ፡ በአንተ ፡ ይፈርድብሃል ። በግ
ልጥ ፡ አይሁዳዊ ፡ የሆነ ፡ አይሁዳዊ ፡ አይደለ
ምና ÷ በግልጥ ፡ በሥጋ ፡ የሚደረግ ፡ መገረዝም ፡
፳፱ መገረዝ ፡ አይደለምና ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ በስውር ፡
አይሁዳዊ ፡ የሆነ ፡ አይሁዳዊ ፡ ነው ÷ መገረዝም ፡
በመንፈስ ፡ የሚደረግ ፡ የልብ ፡ መገረዝ ፡ ነው ፡
እንጂ ፡ በመጽሐፍ ፡ አይደለም ፤ የእርሱ ፡ ምስ
ጋና ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከሰው ፡
አይደለም ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ እንግዲህ ፡ የአይሁዳዊ ፡ ብልጫው ፡ ምንድር ፡
ነው ? ወይስ ፡ የመገረዝ ፡ ጥቅሙ ፡ ምንድር ፡
፪ ነው ? በሁሉ ፡ ነገር ፡ ብዙ ፡ ነው ። አስቀድሞ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ቃላት ፡ አደራ ፡ ተሰጡአቸው ።
፫ ታዲያ ፡ ምንድር ፡ ነው ? የማያምኑ ፡ ቢኖሩ ፡
አለማመናቸው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታማኝነት ፡
፬ ያስቀራልን ? እንዲህ ፡ አይሁን ፤

በቃልህ ፡ ትጸድቅ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ፍርድ ፡
በገባህም ፡ ጊዜ ፡ ትረታ ፡ ዘንድ ፡

ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ÷ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ውሸተኛ ፡
፭ ከሆነ ፡ እግዚአብሔር ፡ እውነተኛ ፡ ይሁን ። ነገር ፡
ግን ፡ ዓመፃችን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ጽድቅ ፡
የሚያስረዳ ፡ ከሆነ ፡ ምን ፡ እንላለን ? ቍጣን ፡
የሚያመጣ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዓመፀኛ ፡ ነውን ?
፮ እንደ ፡ ሰው ፡ልማድ ፡ እላለሁ ። እንዲህ ፡ አይ
ሁን ፤ እንዲህ ፡ ቢሆን ፡ እግዚአብሔር ፡ በዓለም ፡
፯ እንዴት ፡ ይፈርዳል ? በእኔ ፡ ውሸት ፡ ግን ፡ የእ
ግዚአብሔር ፡ እውነት ፡ ለክብሩ ፡ ከላቀ ፡ ስለ ፡
ምን ፡ በእኔ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ኀጢአተኛ ፡ ገና ፡
፰ ይፈረድብኛል ? ስለ ፡ ምንስ ፡ መልካም ፡ እን
ዲመጣ ፡ ክፉ ፡ አናደርግም ? እንዲሁ ፡ ይሰድ
ቡናልና ፡ አንዳንዱም ፡ እንዲሁ ፡ እንድንል ፡
ይናገራሉና ። የእነርሱም ፡ ፍርድ ፡ ቅን ፡ ነው ።
፱ እንግዲህ ፡ ምን ፡ ይሁን ? ከእነርሱ ፡ እንበል
ጣለንን ? ከቶ ፡ አይደለም ፤ አይሁድም ፡ የግ
ሪክ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ከኀጢአት ፡ በታች ፡ እንደ ፡
፲ ሆኑ ፡ አስቀድመን ፡ ከሰናቸዋልና ፤ እንዲህ ፡
ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፦

፲፩ ጻድቅ ፡ የለም ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፤ አስተዋ
ይም ፡ የለም ፤ እግዚአብሔርንም ፡ የሚፈ
፲፪ ልግ ፡ የለም ፤ ሁሉ ፡ ተሳስተዋል ÷ በአን
ድነትም ፡ የማይጠቅሙ ፡ ሆነዋል ፤ ቸር
ነት ፡ የሚያደርግ ፡ የለም ÷ አንድ ፡ ስንኳ ፡
፲፫ የለም ። ጕሮሮአቸው ፡ እንደ ፡ ተከፈተ ፡
መቃብር ፡ ነው ÷ በመላሳቸውም ፡ሸንግለ
ዋል ፤ የእባብ ፡ መርዝ ፡ ከከንፈሮቻቸው ፡
፲፬ በታች ፡ አለ ፤ አፋቸውም ፡ እርግማንና ፡
፲፭ መራርነት ፡ ሞልቶበታል ፤ እግሮቻቸው ፡
፲፮ ደምን ፡ ለማፍሰስ ፡ ፈጣኖች ፡ ናቸው ፤ ጥፋ
ትና ፡ ጕስቍልና ፡ በመንገዳቸው ፡ ይገኛል ÷
፲፯፡፲፰ የሰላምንም ፡ መንገድ ፡ አያውቁም ። በዓ
ይኖቻቸው ፡ ፊት ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍ
ራት ፡ የለም ።

፲፱ አፍም ፡ ሁሉ ፡ ይዘጋ ፡ ዘንድ ፡ ዓለምም ፡ ሁሉ ፡

፪። ፲፩ ፤ ዘዳግ· ፲ ÷ ፲፯ ፤ የሐዋ· ፲ ÷ ፴፬ ። ፲፫ ፤ ማቴ· ፯ ÷ ፳፩ ፤ ያዕ· ፩ ÷ ፳፪—፳፭ ። ፲፭ ፤ የሐዋ· ፲ ÷ ፴፭ ። ፲፯ ፤ መዝ· ፲፱ ÷ ፲፱ ፤ የሐዋ· ፲፯ ÷ ፴፩ ። ፲፯ ፤ ማቴ· ፫ ÷ ፱ ፤ ዮሐ· ፰ ÷ ፴፫ ። ፲፱ ፤ ማቴ· ፲፭ ÷ ፲፬ ። ፳፬ ፤ ኢሳ· ፶፪ ÷ ፭ ፤ ሕዝ· ፴፮ ÷ ፳ ። ፳፯ ፤ ማቴ· ፲፪ ÷ ፵፩ ። ፳፱ ፤ ዘዳግ· ፴ ÷ ፮ ።

፫። ፪ ፤ ዘዳግ· ፬ ÷ ፰ ። ፫ ፤ ዘኍል· ፳፫ ÷ ፲፱ ፤ ፪ ጢሞ· ፪ ÷ ፲፫ ። ፬ ፤ መዝ· ፶ ÷ ፬ ፤ ፻፲፮ ÷ ፲፩ ። ፭ ፤ ኢዮብ ፴፬ ÷ ፲ ። ፯ ፤ ዘፍጥ· ፲፰ ÷ ፳፭ ። ፰ ፤ ዮሐ· ፭ ÷ ፭ ፣ ፲፭ ። ፱ ፤ ገላ· ፫ ÷ ፳፪ ። ፲—፲፪ ፤ መዝ· ፲፬ ÷ ፩—፫ ፤ ፶፫ ÷ ፩—፫ ። ፲፫ ፤ መዝ· ፭ ÷ ፱ ፤ ፻፵ ÷ ፫ ። ፲፬ ፤ መዝ· ፲ ÷ ፯ ። ፲፭—፲፯ ፤ ምሳ· ፩ ÷ ፲፮ ፤ ኢሳ· ፶፱ ÷ ፯ ፣ ፰ ። ፲፰ ፤ መዝ· ፴፮ ÷ ፩ ።

ከእግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ በታች ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ሕግ ፡ የሚናገረው ፡ ሁሉ ፡ ከሕግ ፡ በታች ፡ ላሉት ፡ እንዲናገር ፡ እናውቃለን ፤ ፳ ይህም ፡ የሕግን ፡ ሥራ ፡ በመሥራት ፡ ሥጋ ፡ የለበሰ ፡ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ ፊት ፡ ስለማይጸድቅ ፡ ነው ፤ ኃጢአት ፡ በሕግ ፡ ይታወቃልና ።

፳፩ አሁን ፡ ግን ፡ በሕግና ፡ በነቢያት ፡ የተመሰከረለት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጽድቅ ፡ ያለ ፡ ሕግ ፡ ተገ ፳፪ ልጦአል ÷ እርሱም ÷ ለሚያምኑ ፡ ሁሉ ፡ የሆነ ÷ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በማመን ፡ የሚገኘው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጽድቅ ፡ ነው ፤ ልዩነት ፡ የለ ፳፫ ምና ፤ ሁሉ ፡ ኃጢአትን ፡ ሠርተዋልና ፡ የእግ ፳፬ ዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ ጐድሎአቸዋል ፤ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስም ፡ በሆነው ፡ ቤዛነት ፡ በኩል ፡ ፳፭ እንዲያው ፡ በጸጋው ፡ ይጸድቃሉ ። እርሱንም ፡ እግዚአብሔር ፡ በእምነት ፡ የሚገኝ ፡ በደሙም ፡ የሆነ ፡ ማስተስሪያ ፡ አድርጎ ፡ አቆመው ፤ ይህም ፡ በፊት ፡ የተደረገውን ፡ ኃጢአት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ችሎታ ፤ ስለ ፡ መተው ፡ ጽድቁን ፡ ያሳይ ፡ ፳፮ ዘንድ ፡ ነው ÷ ራሱም ፡ ጻድቅ ፡ እንዲሆን ፡ በኢየሱስም ፡ የሚያምነውን ፡ እንዲያጸድቅ ፡ አሁን ፡ በዚህ ፡ ዘመን ፡ ጽድቁን ፡ ያሳይ ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

፳፯ ትምክህት ፡ እንግዲህ ፡ ወዴት ፡ ነው ? እርሱ ፡ ቀርቶአል ። በየትኛው ፡ ሕግ ፡ ነው ? በሥራ ፡ ሕግ ፡ ነውን ? አይደለም ÷ በእምነት ፡ ሕግ ፡ ነው ፡ ፳፰ እንጂ ። ሰው ፡ ያለ ፡ ሕግ ፡ ሥራ ፡ በእምነት ፡ ፳፱፡፴ እንዲጸድቅ ፡ እንቈጥራለንና ። ወይስ ፡ እግዚአብሔር ፡ የአይሁድ ፡ ብቻ ፡ አምላክ ፡ ነውን ? የአሕዛብስ ፡ ደግሞ ፡ አምላክ ፡ አይደለምን ? አዎን ÷ የተገረዘን ፡ ስለ ፡ እምነት ፡ ያልተገረዘንም ፡ በእምነት ፡ የሚያጸድቅ ፡ አምላክ ፡ አንድ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የአሕዛብ ፡ ደግሞ ፡ አምላክ ፡ ነው ።

፴፩ እንግዲህ ፡ ሕግን ፡ በእምነት ፡ እንሽራለንን ? አይደለም ፤ ሕግን ፡ እናጸናለን ፡ እንጂ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ እንግዲህ ፡ በሥጋ ፡ አባታችን ፡ የሆነ ፡ አብር ፪ ሃም ፡ ምን ፡ አገኘ ፡ እንላለን ? አብርሃም ፡ በሥራ ፡ ጸድቆ ፡ ቢሆን ፡ የሚመካበት ፡ አለውና ÷ ነገር ፡ ፫ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ አይደለም ። መጽሐፍስ ፡ ምን ፡ አለ ? አብርሃምም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመነ ፡ ጽድቅም ፡ ሆኖ ፡ ተቈጠረለት ።

፬ ለሚሠራ ፡ ደመወዝ ፡ እንደ ፡ ዕዳ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ፭ እንደ ፡ ጸጋ ፡ አይቈጠርለትም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለማይሠራ ÷ ኃጢአተኛውንም ፡ በሚያጸድቅ ፡ ለሚያምን ፡ ሰው ፡ እምነቱ ፡ ጽድቅ ፡ ሆኖ ፡ ይቈ ፮ ጠርለታል ። እንደዚህ ፡ ዳዊት ፡ ደግሞ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡ ጽድቅን ፡ ስለሚቈጥርለት ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ብፅዕና ፡ ይናገራል ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡—

ዓመፃቸው ፡ የተሰረየላቸው ፡ ኃጢአታቸውም ፡ የተከደነላቸው ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፤ ፯
ጌታ ፡ ኃጢአቱን ፡ የማይቈጥርበት ፡ ሰው ፡ ብፁዕ ፡ ነው ። ፰

፱ እንግዲህ ፡ ይህ ፡ ብፅዕና ፡ ስለ ፡ መገረዝ ፡ ተነገረ ? ወይስ ፡ ደግሞ ፡ ስለ ፡ አለመገረዝ ? እምነቱ ፡ ለአብርሃም ፡ ጽድቅ ፡ ሆኖ ፡ ተቈጠረለት ፡ ፲ እንላለንና ። እንዴት ፡ ተቈጠረለት ? ተገርዞ ፡ ሳለ ፡ ነውን ? ወይስ ፡ ሳይገረዝ ? ተገርዞስ ፡ አይደለም ÷ ሳይገረዝ ፡ ነበር ፡ እንጂ ። ፲፩ ሳይገረዝም ፡ በነበረው ፡ እምነት ፡ ያገኘው ፡ የጽድቅ ፡ ማኅተም ፡ የሆነ ፡ የመገረዝን ፡ ምልክት ፡ ተቀበለ ፤ ይህም ፡ እነርሱ ፡ ደግሞ ፡ ጻድቃን ፡ ሆነው ፡ ይቈጠሩ ፡ ዘንድ ፡ ሳይገረዙ ፡ ለሚያምኑ ፡ ሁሉ ፡ ፲፪ አባት ፡ እንዲሆን ፡ ነው ÷ ለተገረዙትም ፡ አባት ፡ እንዲሆን ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ ለተገረዙት ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አባታችን ፡ አብርሃም ፡ ሳይገረዝ ፡ የነበረውን ፡ የእምነቱን ፡ ፍለጋ ፡ ደግሞ ፡ ለሚከተሉ ፡ ነው ።

፲፫ የዓለምም ፡ ወራሽ ፡ እንዲሆን ፡ ለአብርሃምና ፡ ለዘሩ ፡ የተሰጠው ፡ የተስፋ ፡ ቃል ፡ በእምነት ፡ ፲፬ ጽድቅ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በሕግ ፡ አይደለም ። ከሕግ ፡ የሆኑትስ ፡ ወራሾች ፡ ከሆኑ ፡ እምነት ፡ ከንቱ ፡ ፲፭ ሆኖአል ፡ የተስፋውም ፡ ቃል ፡ ተሽሮአል ፤ ሕጉ ፡ መቅሠፍትን ፡ ያደርጋልና ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሕግ ፡ በሌለበት ፡ መተላለፍ ፡ የለም ።

፲፮፡፲፯ ስለዚህ ፡ ከሕግ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ከአብርሃም ፡ እምነት ፡ ደግሞ ፡ ለሆነ ፡ ለዘሩ ፡ ሁሉ ፡ የተስፋው ፡ ቃል ፡ እንዲጸና ፡ እንደ ፡ ጸጋ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ በእምነት ፡ ነው ፤ እርሱም ፡— ለብዙ ፡ አሕዛብ ፡ አባት ፡ አደረግሁህ ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ÷ ለሙታን ፡ ሕይወት ፡ በሚሰጥ ፡ የሌለውንም ፡ እንዳለ ፡ አድርጎ ፡ በሚጠራ ፡ በመነበት ፡ በአምላክ ፡ ፊት ፡ የሁላችን ፡ አባት ፡ ነው ። ፲፰ ዘርህ ፡ እንዲሁ ፡ ሊሆን ፡ ነው ፡ እንደ ፡ ተባለ ÷ ተስፋ ፡ በሌለበት ፡ ጊዜ ፡ የብዙ ፡ አሕዛብ ፡ አባት ፡ እንዲሆን ፡ ተስፋ ፡ ይዞ ፡ አመነ ። ፲፱ የመቶ ፡ ዓመትም ፡ ሽማግሌ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ እንደ ፡ ምውት ፡ የሆነውን ፡ የራሱን ፡ ሥጋና ፡ የሳራ ፡ ማኅፀን ፡ ምውት ፡ መሆኑን ፡ በእምነቱ ፡ ሳይደክም ፡ ተመለከተ ፤ ፳፡፳፩ ለእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ እየሰጠ ÷ የሰጠውንም ፡ ተስፋ ፡ ደግሞ ፡ ሊፈጽም ፡ እንዲችል ፡ አጥብቆ ፡ እየተረዳ ÷ በእምነት ፡ በረታ ፡ እንጂ ፡ ባለማመን ፡ ምክንያት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ተስፋ ፡ ቃል ፡ አልተጠራጠረም ። ፳፪ ስለዚህ ፡ ደግሞ ፡ ጽድቅ ፡ ሆኖ ፡ ተቈጠረለት ። ፳፫ ነገር ፡ ግን ፡— ተቈጠረለት ፡ የሚለው ፡ ቃል ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ብቻ ፡ የተ

፫። ፳ ፡ መዝ. ፻፵፪ ፥ ፪ ፤ ገላ. ፪ ፥ ፲፮ ። ፳፪ ፡ የሐዋ. ፲፭ ፥ ፱ ። ፳፫ ፡ ገላ. ፫ ፥ ፳፪ ። ፳፬ ፡ ማቴ. ፳ ፥ ፳፰ ፤ ቲቶ ፫ ፥ ፭ ። ፳፭ ፡ ዘሌዋ. ፲፮ ፥ ፲፭ ፤ ፲፯ ፤ ፩ ዮሐ. ፪ ፥ ፪ ። ፳፰ ፡ የሐዋ. ፲፫ ፥ ፴፱ ፤ ገላ. ፪ ፥ ፲፮ ። ፴፩ ፡ ማቴ. ፭ ፥ ፲፯ ።
፬። ፫ ፡ ዘፍጥ. ፲፭ ፥ ፮ ። ፬ ፡ ማቴ. ፳ ፥ ፲፫ ፤ ፲፭ ። ፭ ፡ ሮሜ. ፫ ፥ ፳፰ ። ፯ ፡ ፰ ፡ መዝ. ፴፪ ፥ ፩ ፤ ፪ ። ፲፩ ፡ ዘፍጥ. ፲፯ ፥ ፲ ። ፲፫ ፡ ዘፍጥ. ፲፯ ፥ ፬—፮ ። ፲፬ ፡ ገላ. ፫ ፥ ፲፰ ፤ ፲፰ ። ፲፭ ፡ ሮሜ. ፯ ፥ ፯ ፤ ፲ ። ፲፯ ፡ ዘፍጥ. ፲፯ ፥ ፭ ። ፲፰ ፡ ዘፍጥ. ፲፭ ፥ ፭ ፤ ዮሐ. ፭ ፥ ፳፭ ። ፲፱ ፡ ዘፍጥ. ፲፯ ፥ ፩ ። ፳ ፡ ዘፍጥ. ፲፰ ፥ ፲፬ ፤ ፲፬ ፥ ፲፬ ። ፳፫ ፡ ሮሜ. ፲፭ ፥ ፬ ።

፬፡፳፭ ዳሩ ፡ አይደለም ፥ ስለ ፡ እኛም ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ስለ ፡ በደላችን ፡ አልፎ ፡ የተሰጠውን ፡ እኛን ፡ ስለ ፡ ማጽደቅም ፡ የተነሣውን ፡ ጌታችንን ፡ ኢየሱስን ፡ ከሙታን ፡ ባስነሣው ፡ ስምናምን ፡ ለእኛ ፡ ይቈጠርልን ፡ ዘንድ ፡ አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ እንግዲህ ፡ በእምነት ፡ ከጸደቅን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ በጌታችን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሰላምን ፡ እንያዝ ፤ ፪ በእርሱም ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ ቆምንበት ፡ ወደዚህ ፡ ጸጋ ፡ በእምነት ፡ መግባትን ፡ አግኝተናል ፤ በእግዚአብሔር ፡ ክብ ፫፡፬ ርም ፡ ተስፋ ፡ እንመካለን ። ይህም ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ መከራ ፡ ትዕግሥትን ፡ እንዲያደርግ ፥ ትዕግሥትም ፡ ፈተናን ፡ ፈተናም ፡ ተስፋን ፡ እንዲያደርግ ፡ እያወቅን ፥ በመ ፭ ከራችን ፡ ደግሞ ፡ እንመካለን ፤ በተሰጠንም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍቅር ፡ በልባችን ፡ ስለ ፡ ፈሰሰ ፡ ተስፋ ፡ አያሳፍርም ።

፮ ገና ፡ ደካሞች ፡ ሳለን ፡ ክርስቶስ ፡ ዘመኑ ፡ ሲደ ፯ ርስ ፡ ስለ ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሞቶአልና ። ስለ ፡ ጻድቅ ፡ የሚሞት ፡ በጭንቅ ፡ ይገኛልና ፤ ስለ ፡ ቸር ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ሊሞት ፡ እንኳ ፡ የሚደፍር ፡ ፰ ምናልባት ፡ ይገኝ ፡ ይሆናል ። ነገር ፡ ግን ፡ ገና ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሳለን ፡ ክርስቶስ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ ሞቶ አልና ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእኛ ፡ ያለውን ፡ የራ ፱ ሱን ፡ ፍቅር ፡ ያስረዳል ። ይልቁንስ ፡ እንግዲህ ፡ አሁን ፡ በደሙ ፡ ከጸደቅን ፡ በእርሱ ፡ ከቍጣው ፡ ፲ እንድናለን ። ጠላቶች ፡ ሳለን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ በልጁ ፡ ሞት ፡ ከታረቅን ፥ ይልቁንም ፡ ከታረቅን ፡ በኋላ ፡ በሕይወቱ ፡ እንድናለን ፤ ፲፩ ይህም ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አሁን ፡ መታረቁን ፡ ባገኘንበት ፡ በጌታችን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በኩል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደግሞ ፡ እንመካለን ።

፲፪ ስለዚህ ፡ ምክንያት ፡ ኃጢአት ፡ በአንድ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ ገባ ፡ በኃጢአትም ፡ ሞት ፥ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአትን ፡ ስላደረጉ ፡ ሞት ፡ ፲፫ ለሰው ፡ ሁሉ ፡ ደረሰ ፤ ሕግ ፡ እስከ ፡ መጣ ፡ ድረስ ፡ ኃጢአት ፡ በዓለም ፡ ነበረና ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ሕግ ፡ ፲፬ በሌለበት ፡ ጊዜ ፡ ኃጢአት ፡ አይቈጠርም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በአዳም ፡ መተላለፍ ፡ ምሳሌ ፡ ኃጢአትን ፡ በልሠሩት ፡ ላይ ፡ እንኳ ፥ ከአዳም ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሙሴ ፡ ድረስ ፡ ሞት ፡ ነግሦ ፤ አዳም ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ ላለው ፡ ለእርሱ ፡ እምሳሉ ፡ ነውና ።

፲፭ ነገር ፡ ግን ፡ ስጦታው ፡ እንደ ፡ በደሉ ፡ መጠን ፡ እንደዚያው ፡ አይደለም ፤ በአንድ ፡ ሰው ፡ በደል ፡ ብዙዎቹ ፡ ሞተዋልና ፥ ነገር ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጸጋና ፡ በአንድ ፡ ሰው ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋ ፡ የሆነው ፡ ስጦታ ፡ ከዚያ ፡ ይልቅ ፡ ለብዙዎች ፡ በዛ ። ፲፮ አንድ ፡ ሰውም ፡ ኃጢአትን ፡ በማድረጉ ፡ እንደ ፡ ሆነው ፡ መጠን ፡ እንደዚያው ፡ ስጦታው ፡ አይደለም ፤ ፍርድ ፡ ከአንድ ፡ ሰው ፡ ለኵነኔ ፡ መጥቶአልና ፥ ስጦታው ፡ ግን ፡ በብዙ ፡ በደል ፡ ለማጽደቅ ፡ መጣ ። ፲፯ በአንዱም ፡ በደል ፡ ሞት ፡ በአንዱ ፡ በኩል ፡ ከነገሠ ፥ ይልቁን ፡ የጸጋን ፡ ብዛትና ፡ የጽድቅን ፡ ስጦታ ፡ ብዛት ፡ የሚቀበሉ ፡ በአንዱ ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በኩል ፡ በሕይወት ፡ ይነግሣሉ ።

፲፰ እንግዲህ ፡ በአንድ ፡ በደል ፡ ምክንያት ፡ ፍርድ ፡ ለኵነኔ ፡ ወደ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ መጣ ፥ እንዲሁም ፡ በአንድ ፡ ጽድቅ ፡ ምክንያት ፡ ስጦታው ፡ ሕይወትን ፡ ለማጽደቅ ፡ ወደ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ መጣ ። ፲፱ በአንዱ ፡ ሰው ፡ አለመታዘዝ ፡ ብዙዎች ፡ ኃጢአተኞች ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፥ እንዲሁ ፡ ደግሞ ፡ በአንዱ ፡ መታዘዝ ፡ ብዙዎች ፡ ጻድቃን ፡ ይሆናሉ ። ፳፡፳፩ በደልም ፡ እንዲበዛ ፡ ሕግ ፡ ጭምር ፡ ገባ ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ ኃጢአት ፡ በበዛበት ፥ ኃጢአት ፡ በሞት ፡ እንደ ፡ ነገሠ ፥ እንዲሁ ፡ ደግሞ ፡ ጸጋ ፡ ከጌታችን ፡ ከኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ የተነሣ ፡ በጽድቅ ፡ ምክንያት ፡ ለዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ይነግሥ ፡ ዘንድ ፥ ጸጋ ፡ ከመጠን ፡ ይልቅ ፡ በለጠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ እንግዲህ ፡ ምን ፡ እንላለን ? ጸጋ ፡ እንዲበዛ ፡ ፪ በኃጢአት ፡ ጸንተን ፡ እንኑርን ? አይደለም ። ለኃጢአት ፡ የሞትን ፡ እኛ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ እንዴት ፡ ፫ አድርገን ፡ በእርሱ ፡ እንኖራለን ? ወይስ ፡ ከክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ፡ የተጠመቅን ፡ ሁላችን ፡ ከሞቱ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተጠመቅን ፡ አታውቁ ፬ ምን ? እንግዲህ ፡ ክርስቶስ ፡ በአብ ፡ ክብር ፡ ከሙታን ፡ እንደ ፡ ተነሣ ፡ እንዲሁ ፡ እኛም ፡ በአዲስ ፡ ሕይወት ፡ እንድንመላለስ ፥ ከሞቱ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ፡ በጥምቀት ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተቀበርን ።

፭ ሞቱንም ፡ በሚመስል ፡ ሞት ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ከተባበርን ፥ ትንሣኤውን ፡ በሚመስል ፡ ትንሣኤ ፡ ደግሞ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ እንተባበራለን ፤ ፮ ከእንግዲህስ ፡ ወዲያ ፡ ለኃጢአት ፡ እንዳንገዛ ፡ የኃጢአት ፡ ሥጋ ፡ ይሻር ፡ ዘንድ ፡ አሮጌው ፡ ሰዋችን ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ተሰቀለ ፡ እናውቃለን ፤ ፯፡፰ የሞተስ ፡ ከኃጢአቱ ፡ ጸድቆአልና ። ነገር ፡ ግን ፡ ከክርስቶስ ፡ ጋር ፡ ከሞትን ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡

፬። ፳፭ ፤ ኢሳ. ፶፫ ፥ ፭ ።
፭። ፩ ፤ ም. ፫ ፡ ፳፰ ፤ ፪ ቆሮ. ፭ ፥ ፲፰ ። ፪ ፤ ኤፌ. ፪ ፥ ፲፰ ፤ ፫ ፥ ፲፪ ። ፫ ፤ ማቴ. ፭ ፥ ፲፪ ፤ ያዕ. ፩ ፥ ፫ ። ፭ ፤ መዝ. ፳፩ ፥ ፳፪ ፤ ፊልጵ. ፩ ፥ ፳ ። ፰ ፤ ዮሐ. ፫ ፥ ፲፮ ፤ ፩ ዮሐ. ፬ ፥ ፲ ። ፱ ፤ ም. ፩ ፥ ፲፰ ። ፲ ፤ ቆላ. ፩ ፥ ፳፩ ፤ ዕብ. ፯ ፥ ፳፭ ። ፲፪ ፤ ዘፍጥ. ፪ ፥ ፲፯ ፤ ፫ ፥ ፮ ። ፲፬ ፤ ፩ ቆሮ. ፲፭ ፥ ፳፪ ፣ ፵፭ ። ፲፰ ፣ ፲፱ ፤ ኢሳ. ፶፫ ፥ ፲፩ ። ፳ ፤ ፩ ጢሞ. ፩ ፥ ፲፫ ፣ ፲፬ ።
፮። ፩ ፤ ም. ፫ ፥ ፰ ። ፪ ፤ ፩ ጴጥ. ፬ ፥ ፩ ። ፬ ፤ ቆላ. ፪ ፥ ፲፪ ። ፮ ፤ ገላ. ፪ ፥ ፳ ፤ ፭ ፥ ፳፬ ። ፯ ፤ ፩ ጴጥ. ፬ ፥ ፩ ። ፰ ፤ ፪ ጢሞ. ፪ ፥ ፲፩ ።

ደግሞ ፡ በሕይወት ፡ እንድንኖር ፡ እናምናለን ፤
፱ ክርስቶስ ፡ ከሙታን ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ እንዳ ይሞት ፡ ሞትም ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ እንዳይገዛው ፡ እና
፲ ውቃለንና ። መሞትን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ፈጽሞ ለኃጢአት ፡ ሞቶአልና ፤ በሕይወት ፡ መኖርን ፡
፲፩ ግን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይኖራል ። እንዲሁም ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ለኃጢአት ፡ እንደ ፡ ሞታችሁ ÷ ግን ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ በጌታችን ፡ ሆናችሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሕያዋን ፡ እንደ ፡ ሆናችሁ ፡ ራሳ ችሁን ፡ ቍጠሩ ።

፲፪ እንግዲህ ፡ ለምኞቱ ፡ እንድትታዘዙ ፡ በሚ
፲፫ ሞት ፡ ሥጋችሁ ፡ ኃጢአት ፡ አይንገሥ ፤ ብል ቶቻችሁንም ፡ የዓመፃ ፡ የጦር ፡ ዕቃ ፡ አድርጋ ችሁ ፡ ለኃጢአት ፡ አታቅርቡ ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ከሙ ታን ፡ ተለይታችሁ ፡ በሕይወት ፡ እንደምትኖሩ ፡ ራሳችሁን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አቅርቡ ÷ ብልቶ ቻችሁንም ፡ የጽድቅ ፡ የጦር ፡ ዕቃ ፡ አድርጋችሁ ፡
፲፬ ለእግዚአብሔር ፡ አቅርቡ ። ኃጢአት ፡ አይገዛ ችሁምና ፤ ከጸጋ ፡ በታች ፡ እንጂ ፡ ከሕግ ፡ በታች ፡ አይደላችሁምና ።

፲፭ እንግዲህ ፡ ምን ፡ ይሁን ? ከጸጋ ፡ በታች ፡ እንጂ ፡ ከሕግ ፡ በታች ፡ ስላይደለን ፡ ኃጢአትን ፡
፲፮ እንሥራን ? አይደለም ። ለመታዘዝ ፡ ባሪያ ዎች ፡ እንድትሆኑ ፡ ራሳችሁን ፡ ለምታቀርቡ ለት ÷ ለእርሱ ፡ ለምትታዘዙለት ፡ ባሪያዎች ፡ እንደ ፡ ሆናችሁ ፡ አታውቁምን ? ወይም ፡ ለሞት ፡ የኃጢአት ፡ ባሪያዎች ፡ ወይም ፡ ለጽድቅ ፡ የመ
፲፯፡፲፰ ታዘዝ ፡ ባሪያዎች ፡ ናችሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ አስቀ ድማችሁ ፡ የኃጢአት ፡ ባሪያዎች ፡ ከሆናችሁ ÷ ለተሰጣችሁለት ፡ ለትምህርት ፡ ዓይነት ፡ ከልባ ችሁ ፡ ስለ ፡ ታዘዛችሁ ÷ ከኃጢአትም ፡ አርነት ፡ ወጥታችሁ ፡ ለጽድቅ ፡ ስለ ፡ ተገዛችሁ ፡ ለእግ
፲፱ ዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ ይሁን ። ስለ ፡ ሥጋችሁ ፡ ድካም ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ልማድ ፡ እላለሁ ። ብል ቶቻችሁ ፡ ዓመፃ ፡ ሊያደርጉ ፡ ለርኵሰትና ፡ ለዓ መፃ ፡ ባሪያዎች ፡ አድርጋችሁ ፡ እንዳቀረባችሁ ÷ እንደዚሁ ፡ ብልቶቻችሁ ፡ ሊቀደሱ ፡ ለጽድቅ ፡ ባሪያዎች ፡ አድርጋችሁ ፡ አሁን ፡ አቅርቡ ።

፳ የኃጢአት ፡ ባሪያዎች ፡ ሳላችሁ ፡ ከጽድቅ ፡
፳፩ ነፃ ፡ ነበራችሁና ። እንግዲህ ፡ ዛሬ ፡ ከምታፍሩ በት ፡ ነገር ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ምን ፡ ፍሬ ፡ ነበራችሁ ?
፳፪ የዚህ ፡ ነገር ፡ መጨረሻው ፡ ሞት ፡ ነውና ። አሁን ፡ ግን ፡ ከኃጢአት ፡ አርነት ፡ ወጥታችሁ ፡ ለእግ ዚአብሔርም ፡ ተገዝታችሁ ÷ ልትቀደሱ ፡ ፍሬ ፡ አላችሁ ፤ መጨረሻውም ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡
፳፫ ነው ። የኃጢአት ፡ ደመወዝ ፡ ሞት ፡ ነውና ፤ የእግዚአብሔር ፡ የጸጋ ፡ ስጦታ ፡ ግን ፡ በክርስ ቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ በጌታችን ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ነው ።

ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ወንድሞች ፡ ሆይ ÷ ሕግን ፡ ለሚያውቁ ፡ እናገ ራለሁና ፡ ሰው ፡ ባለበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ሕግ ፡ እንዲገዛው ፡ አታውቁምን ? ያገባች ፡ ሴት ፡
፪ ባልዋ ፡ በሕይወት ፡ ሲኖር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በሕግ ፡ ታስራለችና ፤ ባልዋ ፡ ቢሞት ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ባል ፡ ከሆነው ፡ ሕግ ፡ ተፈትታለች ።
፫ ስለዚህ ፡ ባልዋ ፡ በሕይወት ፡ ሳለ ፡ ለሌላ ፡ ወንድ ፡ ብትሆን ፡ አመ ንዝራ ፡ ትባላለች ፤ ባልዋ ፡ ቢሞት ፡ ግን ፡ ከሕጉ ፡ አርነት ፡ ወጥታለችና ፡ ለሌላ ፡ ወንድ ፡ ብትሆን ፡ አመንዝራ ፡ አይደለችም ።

፬ እንዲሁ ÷ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ÷ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ በክርስቶስ ፡ ሥጋ ፡ ለሕግ ፡ ተገድላችኋል ፤ ለእ ግዚአብሔር ፡ ፍሬ ፡ እንድናፈራ ÷ እናንተ ፡ ለሌ ላው ÷ ከሙታን ፡ ለተነሣው ÷ ለእርሱ ፡ ትሆኑ ፡
፭ ዘንድ ። በሥጋ ፡ ሳለን ፡ በሕግ ፡ የሚሆን ፡ የኃጢ አት ፡ መሻት ፡ ለሞት ፡ ፍሬ ፡ ሊያፈራ ፡ በብልቶ
፮ ቻችን ፡ ይሠራ ፡ ነበርና ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ለእርሱ ፡ ለታሰርንበት ፡ ስለ ፡ ሞትን ÷ ከሕግ ፡ ተፈትተ ናል ÷ ስለዚህም ፡ በአዲሱ ፡ በመንፈስ ፡ ኑሮ ፡ እንገዛለን ፡ እንጂ ፡ በአሮጌው ፡ በፊደል ፡ ኑሮ ፡ አይደለም ።

፯ እንግዲህ ፡ ምን ፡ እንላለን ? ሕግ ፡ ኃጢአት ፡ ነውን ? አይደለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በሕግ ፡ ባይሆን ፡ ኃጢአትን ፡ ባላወቅሁም ፡ ነበር ፤ ሕጉ ፡ — አት መኝ ፡ ባላለ ፡ ምኞትን ፡ ባላወቅሁም ፡ ነበርና ።
፰ ኃጢአት ፡ ግን ፡ ምክንያት ፡ አግኝቶ ፡ ምኞትን ፡ ሁሉ ፡ በትእዛዝ ፡ ሠራብኝ ፤ ኃጢአት ፡ ያለ ፡ ሕግ ፡
፱ ምውት ፡ ነውና ። እኔም ፡ ዱሮ ፡ ያለ ፡ ሕግ ፡ ሕያው ፡ ነበርሁ ፤ ትእዛዝ ፡ በመጣች ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡
፲ ኃጢአት ፡ ሕያው ፡ ሆነ ፡ እኔም ፡ ሞትሁ ፤ ለሕ ይወትም ፡ የተሰጠችውን ፡ ትእዛዝ ፡ እርስዋን ፡
፲፩ ለሞት ፡ ሆና ፡ አገኘኋት ፤ ኃጢአት ፡ ምክንያት ፡ አግኝቶ ፡ በትእዛዝ ፡ አታለለኝና ፡ በእርስዋም ፡
፲፪ ገደለኝ ። ስለዚህ ፡ ሕጉ ፡ ቅዱስ ፡ ነው ፡ ትእ ዛዚቱም ፡ ቅድስትና ፡ ጻድቅት ፡ በጎም ፡ ናት ።

፲፫ እንግዲህ ፡ በጎ ፡ የሆነው ፡ ነገር ፡ ለእኔ ፡ ሞት ፡ ሆነብኝን ? አይደለም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ኃጢአት ፡ ሆነ ፤ ኃጢአትም ፡ በትእዛዝ ፡ ምክንያት ፡ ያለ ፡ ልክ ፡ ኃጢአተኛ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ÷ ኃጢአትም ፡ እንዲሆን ፡ ይገለጥ ፡ ዘንድ ፡ በጎ ፡ በሆነው ፡ ነገር ፡ ለእኔ ፡ ሞትን ፡ ይሠራ ፡ ነበር ።
፲፬ ሕግ ፡ መንፈሳዊ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እናውቃለንና ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ከኃጢ አት ፡ በታች ፡ ልሆን ፡ የተሸጥሁ ፡ የሥጋ ፡ ነኝ ።
፲፭ የማደርገውን ፡ አላውቅምና ፤ የምጠላውን ፡ ያን ፡ አደርጋለሁና ፡ ዳሩ ፡ ግን ፡ የምወደውን ፡
፲፮ እርሱን ፡ አላደርገውም ። የማልወደውን ፡ ግን ፡ የማደርግ ፡ ከሆንሁ ፡ ሕግ ፡ መልካም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እመሰክራለሁ ። እንደዚህ ፡ ከሆነ ፡ ያን ፡

፮። ፱፤ ራእ· ፩፥፲፰። ፲፩፤ ፪ ቆሮ· ፭፥፲፬፡፲፭። ፲፪፤ መዝ· ፻፲፰፥፻፴፫። ፲፫፤ ሮሜ· ፰፥፲፫። ፲፬፤ ም· ፲፪፥፩። ፳፤ ማቴ· ፮፥፳፬። ፳፩፤ ምዕ· ፲፱፥፲፱፤ ሕዝ· ፴፮፥፴፩። ፳፫፤ ም· ፭፥፲፪፤ ፩ ዮሐ· ፭፥፲፩።
፯። ፪፤ ፩ ቆሮ· ፯፥፴፱። ፫፤ ማቴ· ፭፥፴፪። ፬፤ ፪ ቆሮ· ፲፩፥፪፤ ገላ· ፪፥፲፱። ፭፤ ያዕ· ፩፥፲፭። ፮፤ ም· ፮፥፪፡፬። ፯፤ ም· ፫፥፳፤ ዘፀ· ፳፥፲፯። ፰፤ ም· ፬፥፲፭፤ ፩ ቆሮ· ፲፭፥፶፮። ፲፤ ዘሌዋ· ፲፰፥፭። ፲፩፤ ዘዳግ· ፫፥፲፫። ፲፪፤ መዝ· ፲፱፥፰። ፲፬፤ ኢሳ· ፶፥፩። ፲፭፤ ገላ· ፭፥፲፯።

የማደርገው፡ አሁን፡ እኔ፡ አይደለሁም÷ በእኔ፡ የሚያድር፡ ኃጢአት፡ ነው፡ እንጂ ። ፲፰ በእኔ፡ ማለት፡ በሥጋዬ፡ በጎ፡ ነገር፡ እንዳይኖር፡ አውቃለሁና ፤ ፈቃድ፡ አለኝና÷ መልካሙን፡ ግን፡ ማድረግ፡ የለኝም ። ፲፱ የማልወደውን፡ ክፉን፡ ነገር፡ አደርጋለሁና፡ ዳሩ፡ ግን፡ የምወደውን፡ በጎውን፡ ነገር፡ አላደርገውም ። ፳ የማልወደውን፡ የማደርግ፡ ከሆንሁ፡ ግን፡ ያን፡ የማደርገው፡ አሁን፡ እኔ፡ አይደለሁም÷ በእኔ፡ የሚኖር፡ ኃጢአት፡ ነው፡ እንጂ ።

፳፩ እንግዲያስ፡ መልካሙን፡ አደርግ፡ ዘንድ፡ ስወድ፡ በእኔ፡ ክፉ፡ እንዲያድርብኝ፡ ሕግን፡ አገኛለሁ ። ፳፪ በውስጡ፡ ሰውነቴ፡ በእግዚአብሔር፡ ሕግ፡ ደስ፡ ይለኛልና÷ ፳፫ ነገር፡ ግን፡ በብልቶቼ፡ ከአእምሮዬ፡ ሕግ፡ ጋር፡ የሚዋጋውንና፡ በብልቶቼ፡ ባለ፡ በኃጢአት፡ ሕግ፡ የሚማርከኝን፡ ሌላ፡ ሕግ፡ አያለሁ ። ፳፬ እኔ፡ ምንኛ፡ ጐስቋላ፡ ሰው፡ ነኝ ! ለዚህ፡ ሞት፡ ከተሰጠ፡ ሰውነት፡ ማን፡ ያድነኛል ? ፳፭ በኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ በጌታችን፡ ለእግዚአብሔር፡ ምስጋና፡ ይሁን ። እንግዲያስ፡ እኔ፡ በአእምሮዬ፡ ለእግዚአብሔር፡ ሕግ÷ በሥጋዬ፡ ግን፡ ለኃጢአት፡ ሕግ፡ እገዛለሁ ።

## ምዕራፍ፡ ፰ ።

፩ እንግዲህ፡ በክርስቶስ፡ ኢየሱስ፡ ላሉት፡ አሁን፡ ኵነኔ፡ የለባቸውም ። ፪ በክርስቶስ፡ ኢየሱስ፡ ያለው፡ የሕይወት፡ መንፈስ፡ ሕግ፡ ከኃጢአትና፡ ከሞት፡ ሕግ፡ አርነት፡ አውጥቶኛልና ። ፫ ከሥጋ፡ የተነሣ፡ ስለ፡ ደከመ፡ ለሕግ፡ ያልተቻለውን÷ እግዚአብሔር፡ የገዛ፡ ልጁን፡ በኃጢአተኛ፡ ሥጋ፡ ምሳሌ፡ በኃጢአትም፡ ምክንያት፡ ልኮ፡ አድርጎአልና ፤ ፬ እንደ፡ መንፈስ፡ ፈቃድ፡ እንጂ፡ እንደ፡ ሥጋ፡ ፈቃድ፡ በማንመላለስ፡ በእኛ፡ የሕግ፡ ትእዛዝ፡ ይፈጸም፡ ዘንድ፡ ኃጢአትን፡ በሥጋ፡ ኰነነ ። ፭ እንደ፡ ሥጋ፡ ፈቃድ፡ የሚኖሩ፡ የሥጋን፡ ነገር፡ ያስባሉና÷ እንደ፡ መንፈስ፡ ፈቃድ፡ የሚኖሩ፡ ግን፡ የመንፈስን፡ ነገር፡ ያስባሉ ። ፮ ስለ፡ ሥጋ፡ ማሰብ፡ ሞት፡ ነውና÷ ስለ፡ መንፈስ፡ ማሰብ፡ ግን፡ ሕይወትና፡ ሰላም፡ ነው ። ፯ ስለ፡ ሥጋ፡ ማሰብ፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ጥል፡ ነውና ፤ ለእግዚአብሔር፡ ሕግ፡ አይገዛምና÷ መገዛትም፡ ተስኖታል ፤ ፰ በሥጋ፡ ያሉትም፡ እግዚአብሔርን፡ ደስ፡ ሊያሰኙት፡ አይችሉም ።

፱ እናንተ፡ ግን፡ የእግዚአብሔር፡ መንፈስ፡ በእናንተ፡ ዘንድ፡ ቢኖር÷ በመንፈስ፡ እንጂ፡ በሥጋ፡ አይደላችሁም ። የክርስቶስ፡ መንፈስ፡ የሌለው፡ ከሆነ፡ ግን፡ ይኸው፡ የእርሱ፡ ወገን፡ አይደለም ። ፲ ክርስቶስ፡ በእናንተ፡ ውስጥ፡ ቢሆን፡ ሰውነታችሁ፡ በኃጢአት፡ ምክንያት፡ የሞተ፡ ነው÷ መንፈሳችሁ፡ ግን፡ በጽድቅ፡ ምክንያት፡ ሕያው፡ ነው ። ፲፩ ነገር፡ ግን፡ ኢየሱስን፡ ከሙታን፡ ያስነሣው፡ የእርሱ፡ መንፈስ፡ በእናንተ፡ ዘንድ፡ ቢኖር÷ ክርስቶስ፡ ኢየሱስን፡ ከሙታን፡ ያስነሣው፡ እርሱ፡ በእናንተ፡ በሚኖረው፡ በመንፈሱ÷ ለሚሞተው፡ ሰውነታችሁ፡ ደግሞ፡ ሕይወትን፡ ይሰጠዋል ።

፲፪ እንግዲህ÷ ወንድሞች፡ ሆይ÷ ዕዳ፡ አለብን÷ እንደ፡ ሥጋ፡ ፈቃድ፡ ግን፡ እንኖር፡ ዘንድ፡ በሥጋ፡ አይደለም ። ፲፫ እንደ፡ ሥጋ፡ ፈቃድ፡ ብትኖሩ፡ ትሞቱ፡ ዘንድ፡ አላችሁና ፤ በመንፈስ፡ ግን፡ የሰውነትን፡ ሥራ፡ ብትገድሉ፡ በሕይወት፡ ትኖራላችሁ ። ፲፬ በእግዚአብሔር፡ መንፈስ፡ የሚመሩ፡ ሁሉ፡ እነዚህ፡ የእግዚአብሔር፡ ልጆች፡ ናቸውና ። ፲፭ አባ፡ አባት፡ ብለን፡ የምንጮኽበትን፡ የልጅነትን፡ መንፈስ፡ ተቀበላችሁ፡ እንጂ፡ እንደ፡ ገና፡ ለፍርሃት፡ የባርነትን፡ መንፈስ፡ አልተቀበላችሁምና ። ፲፮ የእግዚአብሔር፡ ልጆች፡ መሆናችንን፡ ያ፡ መንፈስ፡ ራሱ፡ ከመንፈሳችን፡ ጋር፡ ይመሰክራል ። ፲፯ ልጆች፡ ከሆንን፡ ወራሾች፡ ደግሞ፡ ነን ፤ ማለት፡ የእግዚአብሔር፡ ወራሾች፡ ነን÷ አብረንም፡ ደግሞ፡ እንድንከብር፡ አብረን፡ መከራ፡ ብንቀበል፡ ከክርስቶስ፡ ጋር፡ አብረን፡ ወራሾች፡ ነን ።

፲፰ ለእኛም፡ ይገለጥ፡ ዘንድ፡ ካለው፡ ክብር፡ ጋር፡ ቢመዛዘን፡ የአሁኑ፡ ዘመን፡ ሥቃይ፡ ምንም፡ እንዳይደለ፡ አስባለሁ ። ፲፱ የፍጥረት፡ ናፍቆት፡ የእግዚአብሔርን፡ ልጆች፡ መገለጥ፡ ይጠባበቃልና ። ፳ ፍጥረት፡ ለከንቱነት፡ ተገዝቶአልና÷ በተስፋ፡ በላስገዛው፡ ነው፡ እንጂ፡ በፈቃዱ፡ አይደለም ፤ ፳፩ ተስፋውም፡ ፍጥረት፡ ራሱ፡ ደግሞ፡ ከጥፋት፡ ባርነት፡ ነፃነት፡ ወጥቶ፡ ለእግዚአብሔር፡ ልጆች፡ ወደሚሆን፡ ክብር፡ ነፃነት፡ እንዲደርስ፡ ነው ። ፳፪ ፍጥረት፡ ሁሉ፡ እስከ፡ አሁን፡ ድረስ፡ አብሮ፡ በመቃተትና፡ በምጥ፡ መኖሩን፡ እናውቃለንና ። ፳፫ እርሱም፡ ብቻ፡ አይደለም÷ ነገር፡ ግን፡ የመንፈስ፡ በኵራት፡ ያለን፡ ራሳችን፡ ደግሞ፡ የሰውነታችን፡ ቤዛ፡ የሆነውን፡ ልጅነት፡ እየተጠባበቅን፡ ራሳችን፡ በውስጣችን፡ እንቃትታለን ። ፳፬ በተስፋ፡ ድነናልና ፤ ነገር፡ ግን፡ ተስፋ፡ የሚደረግበቱ፡ ነገር፡ ቢታይ፡ ተስፋ፡ አይደለም ፤ የሚያየውንማ፡ ማን፡ ተስፋ፡ ያደርገዋል ? ፳፭ የማናየውን፡ ግን፡ ተስፋ፡ ብናደርገው፡ በትዕግሥት፡ እንጠባበቃለን ።

---

፯። ፳፪፤ መዝ. ፩÷፪፤ ፩፻፲፱÷፭። ፳፫፤ ቍ. ፲፮። ፳፭፤ ፩ ቆሮ. ፲፭÷፶፯።

፰። ፪፤ ፪ ቆሮ. ፫÷፮፤ ፲፯። ፫፤ የሐዋ. ፲፫÷፴፱፤ ዕብ. ፯÷፲፰። ፬፤ ፭፤ ገላ. ፭÷፲፮። ፮፤ ያዕ. ፬÷፬። ፱፤ የሐ. ፫÷፮። ፲፤ ፩ ቆሮ. ፫÷፲፮። ፲፩፤ ቈላ. ፫÷፬። ፲፫፤ ፩ ጴጥ. ፩÷፲፬፤ ገላ. ፮÷፰፤ ፭፤ ማር. ፲፬÷፴፮። ፲፭፤ ገላ. ፬÷፭፤ ኤፌ. ፩÷፭፤ ፪ ጢሞ. ፩÷፯። ፲፮፤ ፪ ቆሮ. ፩÷፳፪። ፲፯፤ ፩ ዮሐ. ፫÷፩። ፳፤ መክ. ፩÷፪፤ ዘፍ. ፫÷፲፯—፲፱። ፳፩፤ ፪ ጴጥ. ፫÷፲፫፤ ራእ. ፳፩÷፩። ፳፪፤ ኤር. ፲፪÷፬፤ ፲፩፤ ሆሴ. ፬÷፫። ፳፫፤ ፪ ቆሮ. ፭÷፪—፬። ፳፬፤ ፪ ቆሮ. ፭÷፯።

፳፮ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ መንፈስ ፡ ድካማችንን ፡ ያግዛል ፤ እንዴት ፡ እንድንጸልይ ፡ እንደሚገ ባን ፡ አናውቅምና ፤ ነገር ፡ ግን ፡ መንፈስ ፡ ራሱ ፡ ፳፯ በማይነገር ፡ መቃተት ፡ ይማልድልናል ፤ ልብ ንም ፡ የሚመረምረው ፡ የመንፈስ ፡ አሳብ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያውቃል ፤ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ስለ ፡ ቅዱሳን ፡ ይማልዳልና ።

፳፰ እግዚአብሔርንም ፡ ለሚወዱት ፡ እንደ ፡ አሳ ቡም ፡ ለተጠሩት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ለበጎ ፡ እንዲደ ፳፱ ረግ ፡ እናውቃለን ። ልጁ ፡ በብዙ ፡ ወንድሞች ፡ መካከል ፡ በኵር ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፤ አስቀድሞ ፡ ያወቃቸው ፡ የልጁን ፡ መልክ ፡ እንዲመስሉ ፡ ፴ አስቀድሞ ፡ ደግሞ ፡ ወስኖአልና ፤ አስቀድ ሞም ፡ የወሰናቸውን ፡ እነዚህን ፡ ደግሞ ፡ ጠራ ቸው ፤ የጠራቸውንም ፡ እነዚህን ፡ ደግሞ ፡ አጸደቃቸው ፤ ያጸደቃቸውንም ፡ እነዚህን ፡ ደግሞ ፡ አከበራቸው ።

፴፩ እንግዲህ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ምን ፡ እንላለን ? እግዚአብሔር ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ከሆነ ፡ ማን ፡ ይቃ ፴፪ ወመናል ? ለገዛ ፡ ልጁ ፡ ያልራራለት ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ሁላችን ፡ አሳልፎ ፡ የሰጠው ፡ ያው ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ደግሞ ፡ ሁሉን ፡ ነገር ፡ እንዲያው ፡ ፴፫ እንዴት ፡ አይሰጠንም ? እግዚአብሔር ፡ የመ ረጣቸውን ፡ ማን ፡ ይከሳቸዋል ? የሚያጸድቅ ፡ ፴፬ እግዚአብሔር ፡ ነው ፤ የሚኰንንስ ፡ ማን ፡ ነው ? የሞተው ፤ ይልቁንም ፡ ከሙታን ፡ የተነሣው ፤ በእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ያለው ፤ ደግሞ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ የሚማልደው ፡ ክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ነው ። ፴፭ ከክርስቶስ ፡ ፍቅር ፡ ማን ፡ ይለየናል ? መከራ ፤ ወይስ ፡ ጭንቀት ፤ ወይስ ፡ ስደት ፤ ወይስ ፡ ራብ ፤ ወይስ ፡ ራቁትነት ፤ ወይስ ፡ ፍርሃት ፤ ወይስ ፡ ሰይፍ ፡ ነውን ?

፴፮ ስለ ፡ አንተ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ እንገደላለን ፤
እንደሚታረዱ ፡ በጎች ፡ ተቈጠርን ፡

ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ነው ።

፴፯ በዚህ ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ በወደደን ፡ በእርሱ ፡ ከአሸ ፴፰ ናፊዎች ፡ እንበልጣለን ። ሞት ፡ ቢሆን ፤ ሕይወ ትም ፡ ቢሆን ፤ መላእክትም ፡ ቢሆኑ ፤ ግዛትም ፡ ቢሆን ፤ ያለውም ፡ ቢሆን ፤ የሚመጣውም ፡ ፴፱ ቢሆን ፤ ኃይላትም ፡ ቢሆኑ ፤ ከፍታም ፡ ቢሆን ፤ ዝቅታም ፡ ቢሆን ፤ ልዩ ፡ ፍጥረትም ፡ ቢሆን ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ በጌታችን ፡ ካለ ፡ ከእግዚ አብሔር ፡ ፍቅር ፡ ሊለየን ፡ እንዳይችል ፡ ተረድ ቼአለሁ ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ፪ ብዙ ፡ ኀዘን ፡ የማያቋርጥም ፡ ጭንቀት ፡ በልቤ ፡ አለብኝ ፡ ስል ፡ በክርስቶስ ፡ ሆኜ ፡ እውነትን ፡ እናገራለሁ ፤ አልዋሽምም ፤ ሕሊናዬም ፡ በመ ፫ ንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ይመሰክርልኛል ። በሥጋ ፡ ዘመ ዶቼ ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ ስለ ፡ ወንድሞቼ ፡ ከክርስቶስ ፡ ተለይቼ ፡ እኔ ፡ ራሴ ፡ የተረገምሁ ፡ እንድሆን ፡ ፬ እጸልይ ፡ ነበርና ። እነርሱ ፡ እስራኤላውያን ፡ ናቸውና ፤ ልጅነትና ፡ ክብር ፡ ኪዳንም ፡ የሕ ግም ፡ መሰጠት ፡ የመቅደስም ፡ ሥርዓት ፡ የተስ ፭ ፋውም ፡ ቃላት ፡ ለእነርሱ ፡ ናቸውና ፤ አባቶ ችም ፡ ለእነርሱ ፡ ናቸውና ፤ ከእነርሱም ፡ ክርስ ቶስ ፡ በሥጋ ፡ መጣ ፤ እርሱም ፡ ከሁሉ ፡ በላይ ፡ ሆኖ ፡ ለዘላለም ፡ የተባረከ ፡ አምላክ ፡ ነው ፤ አሜን ።

፮ ነገር ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ የተሻረ ፡ አይደለም ። እነዚህ ፡ ከእስራኤል ፡ የሚወለዱ ፡ ፯ ሁሉ ፡ እስራኤል ፡ አይደሉምና ፤ የአብርሃምም ፡ ዘር ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ ሁላቸው ፡ ልጆች ፡ አይደሉም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ — በይስሐቅ ፡ ዘር ፡ ይጠራልሃል ፡ ፰ ተብለ ። ይህም ፤ የተስፋ ፡ ቃል ፡ ልጆች ፡ ዘር ፡ ሆነው ፡ ይቈጠራሉ ፡ እንጂ ፡ እነዚህ ፡ የሥጋ ፡ ልጆች ፡ የሆኑ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ አይደ ፱ ሉም ፡ ማለት ፡ ነው ። ይህ ፡ — በዚህ ፡ ጊዜ ፡ እመ ጣለሁ ፡ ለሳራም ፡ ልጅ ፡ ይሆንላታል ፡ የሚል ፡ ፲ የተስፋ ፡ ቃል ፡ ነውና ። ይህ ፡ ብቻ ፡ አይደ ለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ርብቃ ፡ ደግሞ ፡ ከአንዱ ፡ ከአ ፲፩ ባታችን ፡ ከይስሐቅ ፡ በፀነሰች ፡ ጊዜ ፤ ልጆቹ ገና ፡ ሳይወለዱ ፤ በጎ ፡ ወይም ፡ ክፉ ፡ ምንም ፡ ሳያደርጉ ፤ ከጠሪው ፡ እንጂ ፡ ከሥራ ፡ ሳይሆን ፡ በምርጫ ፡ የሚሆን ፡ የእግዚአብሔር ፡ አሳብ ፡ ፲፪ ይጸና ፡ ዘንድ ፤ ለእርስዋ ፡ — ታላቁ ፡ ለታናሹ ፡ ፲፫ ይገዛል ፡ ተባለላት ። ያዕቆብን ፡ ወደድሁ ፡ ኤሳ ውን ፡ ግን ፡ ጠላሁ ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ነው ።

፲፬ እንግዲህ ፡ ምን ፡ እንላለን ? በእግዚአብሔር ፡ ፲፭ ዘንድ ፡ ዓመፃ ፡ አለ ፡ ወይ ? አይደለም ። ለሙሴ ፡ — የምምረውን ፡ ሁሉ ፡ እምረዋለሁ ፡ ለምራራለ ፲፮ ትም ፡ ሁሉ ፡ እራራለታለሁ ፡ ይላልና ። እንግ ዲህ ፡ ምሕረት ፡ ለወደደ ፡ ወይም ፡ ለሮጠ ፡ አይደ ለም ፤ ከሚምር ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ነው ፡ እንጂ ። ፲፯ መጽሐፍ ፡ ፈርዖንን ፡ — ኃይሌን ፡ በአንተ ፡ አሳይ ፡ ዘንድ ፡ ስሜም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ይነገር ፡ ዘንድ ፡ ፲፰ ለዚህ ፡ አስነሣሁህ ፡ ይላልና ። እንግዲህ ፡ የሚ ወደውን ፡ ይምረዋል ፤ የሚወደውንም ፡ እል

፰። [illegible]

፱። [illegible]

ከኛ ፡ ያደርገዋል ።

፲፱ እንግዲህ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ ድረስ ፡ ይነቅፋል ? ፈቃዱንስ ፡ የሚቃወም ፡ ማን ፡ ነው ? ትለኛ ፡ ይሆናል ። ፳ ነገር ፡ ግን ÷ አንተ ፡ ሰው ፡ ሆይ ÷ ለእግዚአብሔር ፡ የምትመልስ ፡ ማን ፡ ነህ ? ሥራ ፡ ሠሪውን — ስለ ፡ ምን ፡ እንዲህ ፡ አድር ፳፩ ገህ ፡ ሠራኸኝ ፡ ይለዋልን ? ወይም ፡ ሸክላ ፡ ሠሪ ፡ ከአንዱ ፡ ጭቃ ፡ ክፍል ፡ አንዱን ፡ ዕቃ ፡ ለክብር ፡ አንዱንም ፡ ለውርደት ፡ ሊሠራ ፡ በጭቃ ፡ ፳፪፡፳፫ ላይ ፡ ሥልጣን ፡ የለውምን ? ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ቍጣውን ፡ ሊያሳይ ፡ ኃይሉንም ፡ ሊገልጥ ፡ ወዶ ÷ አስቀድሞ ፡ ለክብር ፡ ባዘጋጃቸው ፡ በምሕረት ፡ ዕቃዎች ፡ ላይ ፡ የክብሩን ፡ ባለ ፡ ጠግነት ፡ ይገልጥ ፡ ዘንድ ÷ ለጥፋት ፡ የተዘጋጁትን ፡ የቍጣ ፡ ዕቃዎች ፡ በብዙ ፡ ትዕግሥት ፡ ፳፬ ከቻለ ÷ እንዴት ፡ ነው ? የምሕረቱ ፡ ዕቃዎችም ፡ ከአይሁድ ፡ ብቻ ፡ አይደሉም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ከአ ፳፭ ሕዛብ ፡ ደግሞ ፡ የጠራን ፡ እኛ ፡ ነን ። እንዲሁ ፡ ደግሞ ፡ በሆሴዕ ፡—

> ሕዝቤ ፡ ያልሆነውን ፡ ሕዝቤ ፡ ብዬ ÷ ያልተወደደችውንም ፡ የተወደደችው ፡ ብዬ ፡
> ፳፮ እጠራለሁ ፤ እናንተ ፡ ሕዝቤ ፡ አይደላችሁም ፡ በተባለላቸውም ፡ ስፍራ ፡ በዚያ ፡ የሕያው ፡ እግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ተብለው ፡ ይጠራሉ ፡

ይላል ።

፳፯፡፳፰ ኢሳይያስም ፡— የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ቍጥር ፡ ምንም ፡ እንደ ፡ በሕር ፡ አሸዋ ፡ ቢሆን ፡ ቅሬታው ፡ ይድናል ፤ ጌታ ፡ ነገሩን ፡ ፈጽሞና ፡ ቈርጦ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ያደርገዋልና ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ እስራ ፳፱ ኤል ፡ ይጮኻል ። ኢሳይያስም ፡ እንደዚሁ ፡—

> ጌታ ፡ ፀባዖት ፡ ዘር ፡ ባላስቀረልን ፡ እንደ ፡ ሰዶም ፡ በሆንን ፡ ገሞራንም ፡ በመሰልን ፡ ነበር ፡

ብሎ ፡ አስቀድሞ ፡ ተናገረ ።

፴ እንግዲህ ፡ ምን ፡ እንላለን ? ጽድቅን ፡ ያልተከተሉት ፡ አሕዛብ ፡ ጽድቅን ፡ አገኙ ÷ እርሱ ፡ ፴፩ ግን ፡ ከእምነት ፡ የሆነ ፡ ጽድቅ ፡ ነው ፤ እስራኤል ፡ ግን ፡ የጽድቅን ፡ ሕግ ፡ እየተከተሉ ፡ ወደ ፡ ፴፪፡፴፫ ሕግ ፡ አልደረሱም ። ይህስ ፡ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ? በሥራ ፡ እንጂ ፡ በእምነት ፡ ጽድቅን ፡ ስላልተከተሉ ፡ ነው ፤

> እነሆ ÷ በጽዮን ፡ የእንቅፋት ፡ ድንጋይና ፡ የማሰናከያ ፡ ዓለት ፡ አኖራለሁ ፡ በእርሱም ፡ የሚያምን ፡ አያፍርም ፡

ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ በእንቅፋት ፡ ድንጋይ ፡ ተሰናከሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ ወንድሞች ፡ ሆይ ÷ የልቤ ፡ በጎ ፡ ፈቃድና ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልመናዬ ፡ ፪ እንዲድኑ ፡ ነው ። በእውቀት ፡ አይቅኑ ፡ እንጂ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እንዲቀኑ ፡ እመሰክርላቸዋ ፫ ለሁና ። የእግዚአብሔርን ፡ ጽድቅ ፡ ሳያውቁ ፡ የራሳቸውንም ፡ ጽድቅ ፡ ሊያቆሙ ፡ ሲፈልጉ ÷ ፬ ለእግዚአብሔር ፡ ጽድቅ ፡ አልተገዙም ። የሚያምኑ ፡ ሁሉ ፡ ይጸድቁ ፡ ዘንድ ፡ ክርስቶስ ፡ የሕግ ፡ ፍጻሜ ፡ ነውና ።

፭ ሙሴ ፡ ከሕግ ፡ የሆነውን ፡ ጽድቅ ፡ የሚያደርገው ፡ ሰው ፡ በእርሱ ፡ በሕይወት ፡ እንዲኖር ፡ ፮ ጽፎአልና ። ከእምነት ፡ የሆነ ፡ ጽድቅ ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— በልብህ ፡— ማን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ይወጣል ? አትበል ፤ ይህ ፡ ክርስቶ ፯ ስን ፡ ለማውረድ ፡ ነው ፤ ወይም ፡— በልብህ ፡— ወደ ፡ ጥልቁ ፡ ማን ፡ ይወርዳል ? አትበል ፤ ይህ ፡ ክርስቶስን ፡ ከሙታን ፡ ለማውጣት ፡ ነው ። ፰ ነገር ፡ ግን ፡ ምን ፡ ይላል ? በአፍህ ፡ በልብህም ፡ ሆኖ ፡ ቃሉ ፡ ቀርቦልሃል ፤ ይህም ፡ የምንሰብ ፱ ከው ፡ የእምነት ፡ ቃል ፡ ነው ። ኢየሱስ ፡ ጌታ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በአፍህ ፡ ብትመሰክር ፡ እግዚአብሔርም ፡ ከሙታን ፡ እንዳስነሣው ፡ በልብህ ፡ ብታ ፲ ምን ፡ ትድናለህና ፤ ሰው ፡ በልቡ ፡ አምኖ ፡ ይጸድቃልና ፡ በአፉም ፡ መስክሮ ፡ ይድናልና ። ፲፩ መጽሐፍ ፡— በእርሱ ፡ የሚያምን ፡ ሁሉ ፡ አያ ፲፪ ፍርም ፡ ይላልና ። በአይሁዳዊና ፡ በግሪክ ፡ ሰው ፡ መካከል ፡ልዩነት ፡ የለምና ፤ አንዱ ፡ ጌታ ፡ የሁሉ ፡ ጌታ ፡ ነውና ÷ ለሚጠሩትም ፡ ሁሉ ፡ ፲፫ ባለ ፡ ጠጋ ፡ ነው ፤ የጌታን ፡ ስም ፡ የሚጠራ ፡ ሁሉ ፡ ይድናልና ።

፲፬ እንግዲህ ፡ ያላመኑበትን ፡ እንዴት ፡ አድርገው ፡ ይጠሩታል ? ባልሰሙትስ ፡ እንዴት ፡ ያምናሉ ? ያለ ፡ ሰባኪስ ፡ እንዴት ፡ ይሰማሉ ? ፲፭ መልካሙን ፡ የምሥራች ፡ የሚያወሩ ፡ እግሮቻቸው ፡ እንዴት ፡ ያማሩ ፡ ናቸው ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ፲፮ ተጻፈ ፡ ካልተላኩ ፡ እንዴት ፡ ይሰብካሉ ? ነገር ፡ ግን ፡ ሁሉ ፡ ለምሥራቹ ፡ ቃል ፡ አልታዘዙም ። ኢሳይያስ ፡— ጌታ ፡ ሆይ ÷ ምስክርነታችንን ፡ ፲፯ ማን ፡ አመነ ? ብሎአልና ። እንግዲያስ ፡ እምነት ፡ ከመስማት ፡ ነው ፡ መስማትም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ነው ።

፲፰ ላሉ ፡ ግን ፡— ባይሰሙ ፡ ነው ፡ ወይ ? እላለሁ ። በእውነት ፡—

> ድምፃቸው ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ቃላቸውም ፡ እስከ ፡ ዓለም ፡ ዳርቻ ፡ ወጣ ።

፲፱ ነገር ፡ ግን ፡— እስራኤል ፡ በያውቁ ፡ ነው ፡ ወይ ?

---

፱። ፳፪ ምሳ. ፲፮ ፥ ፬። ፳፫ ምሳ. ፰ ፥ ፴፱። ፳፬ ምሳ. ፫ ፥ ፳፱። ፳፭ ሆሴ. ፪ ፥ ፳፫። ፳፮ ሆሴ. ፩ ፥ ፲። ፳፯ ፡ ፳፰ ኢሳ. ፲ ፥ ፳፪ ፡ ፳፫። ፳፱ ኢሳ. ፩ ፥ ፱ ፤ ዘፍጥ. ፲፱ ፥ ፳፬ ፡ ፳፭። ፴፪ ሮሜ. ፪ ፥ ፳፰ ፡ ፳፱። ፴፫ ኢሳ. ፳፰ ፥ ፲፮ ፤ ፰ ፥ ፲፬።

፲። ፪ ፤ የሐዋ. ፳፪ ፥ ፫። ፬ ፤ ማቴ. ፭ ፥ ፲፯ ፤ ገላ. ፫ ፥ ፳፬። ፭ ፤ ዘሌዋ. ፲፰ ፥ ፭። ፮—፰ ፤ ዘዳግ. ፴ ፥ ፲፪—፲፬። ፱ ፤ ማቴ. ፲ ፥ ፴፪። ፲፩ ፤ ምሳ. ፱ ፥ ፴፫። ፲፪ ፤ ምሳ. ፫ ፥ ፳፪ ፡ ፳፱ ፤ የሐዋ. ፲ ፥ ፴፬ ፡ ፴፭። ፲፫ ፤ ኢዩ. ፪ ፥ ፴፪። ፲፭ ፤ ኢሳ. ፶፪ ፥ ፯ ፤ የሐ. ፲፪ ፥ ፴፰። ፲፮ ፤ ኢሳ. ፶፫ ፥ ፩። ፲፰ ፤ መዝ. ፲፱ ፥ ፬። ፲፱ ፤ ዘዳግ. ፴፪ ፥ ፳፩።

እላለሁ ። ሙሴ ፡ አስቀድሞ ፡—

እኔ ፡ ሕዝብ ፡ በማይሆነው ፡ አስቀናችኋለሁ ፡ በማያስተውልም ፡ ሕዝብ ፡ አስቈጣችኋለሁ ፡

፳ ብሎአል ። ኢሳይያስም ፡ ደፍሮ ፡—

ላልፈለጉኝ ፡ ተገኘሁ ÷ ላልጠየቁኝም ፡ ተገለጥሁ ፡

፳፩ አለ ። ስለ ፡ እስራኤል ፡ ግን ፡— ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ወደማይታዘዝና ፡ ወደሚቃወም ፡ ሕዝብ ፡ እጆቼን ፡ ዘረጋሁ ፡ ይላል ።

ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ እንግዲህ ፡— እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ ጣላቸውን ? እላለሁ ። አይደለም ፤ እኔ ፡ ደግሞ ፡ እስራኤላዊና ፡ ከአብርሃም ፡ ዘር ፡ ከብንያምም ፡

፪ ወገን ፡ ነኝና ። እግዚአብሔር ፡ አስቀድሞ ፡ ያወቃቸውን ፡ ሕዝብ ፡ አልጣላቸውም ። መጽሐፍ ፡ ስለ ፡ ኤልያስ ፡ በተጻፈው ፡ የሚለውን ÷ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እስራኤልን ፡ እንዴት ፡ እንደሚ

፫ ከስ ÷ አታውቁምን ? ጌታ ፡ ሆይ ÷ ነቢያትህን ፡ ገደሉ ፡ መሠዊያዎችህንም ፡ አፈረሱ ፡ እኔም ፡

፬ ብቻዬን ፡ ተረሁ ፡ ነፍሴንም ፡ ይሹአታል ። ነገር ፡ ግን ፡ አምላካዊ ፡ መልስ ፡ ምን ፡ አለው ? ለበ አል ፡ ያልሰገዱትን ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡ ሰዎች ፡ ለእኔ ፡

፭ አስቀርቼአለሁ ። እንደዚሁም ፡ በአሁን ፡ ዘመን ፡ ደግሞ ፡ በጸጋ ፡ የተመረጡ ፡ ቅሬታዎች ፡ አሉ ።

፮ በጸጋ ፡ ከሆነ ፡ ግን ፡ ከሥራ ፡ መሆኑ ፡ ቀርቶአል ፤ ጸጋ ፡ ያስዚያ ፡ ጸጋ ፡ መሆኑ ፡ ቀርቶአል ።

፯ እንግዲህ ፡ ምንድር ፡ ነው ? እስራኤል ፡ የሚፈልጉትን ፡ አላገኙትም ፤ የተመረጡት ፡ ግን ፡

፰ አገኙት ፤ ሌሎቹም ፡ ደነዘዙ ፤ እንዲሁም ፡— ዓይኖቻቸው ፡ እንዳያዩ ፡ ጆሮቻቸውም ፡ እንዳይሰሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ የእንቅልፍ ፡ መንፈስን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ሰጣቸው ፡ ተብሎ ፡ ተጽፎ

፱ አል ። ዳዊትም ፡—

ማዕዳቸው ፡ ወጥመድና ፡ አሽክላ ፡ ማሰና

፲ ከያም ፡ ፍዳም ፡ ይሁንባቸው ፤ ዓይኖቻቸው ፡ እንዳያዩ ፡ ይጨልሙ ÷ ጀርባቸውንም ፡ ዘወትር ፡ አጕብጥ ፡

ብሎአል ።

፲፩ እንግዲህ ፡— የተሰናከሉ ፡ እስኪወድቁ ፡ ድረስ ፡ ነውን ? እላለሁ ። አይደለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እነርሱን ፡ ያስቀናቸው ፡ ዘንድ ፡ በእነርሱ ፡

፲፪ በደል ፡ መዳን ፡ ለአሕዛብ ፡ ሆነ ። ዳሩ ፡ ግን ፡ በደላቸው ፡ ለዓለም ፡ ባለ ፡ ጠግነት ÷ መሸነፋቸውም ፡ ለአሕዛብ ፡ ባለ ፡ ጠግነት ፡ ከሆነ ÷ ይልቁንስ ፡ መሙላታቸው ፡ እንዴት ፡ ይሆን ?

፲፫፡፲፬ ለእናንተም ፡ ለአሕዛብ ፡ እናገራለሁ ። እኔ ፡ የአሕዛብ ፡ ሐዋርያ ፡ በሆንሁ ፡ መጠን ፡ ሥጋዬ ፡ የሆኑትን ፡ አስቀንቼ ፡ ምናልባት ፡ ከእነርሱ ፡ አንዳንዱን ፡ አድን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አገልግሎቴን ፡ አከ

፲፭ ብራለሁ ። የእነርሱ ፡ መጣል ፡ ለዓለም ፡ መታረቅ ፡ ከሆነ ፡ ከሙታን ፡ ከሚመጣ ፡ ሕይወት ፡

፲፮ በቀር ፡ መመለሳቸው ፡ ምን ፡ ይሆን ? በኵራቱም ፡ ቅዱስ ፡ ከሆነ ፡ ቡሆው ፡ ደግሞ ፡ ቅዱስ ፡ ነው ፤ ሥሩም ፡ ቅዱስ ፡ ከሆነ ፡ ቅርንጫፎቹ ፡ ደግሞ ፡ ቅዱሳን ፡ ናቸው ።

፲፯ ነገር ፡ ግን ፡ ከቅርንጫፎች ፡ አንዳንዱ ፡ ቢሰበሩ ፡ አንተም ፡ የበረሀ ፡ ወይራ ፡ የሆንሀ ፡ በመካከላቸው ፡ ገብተህ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ የወይራ ፡ ዘይት ፡ ከሚወጣው ፡ ሥር ፡ ተካፋይ ፡ ከሆንህ ÷

፲፰ በቅርንጫፎች ፡ ላይ ፡ አትመካ ፤ ብትመካባቸው ፡ ግን ፡ ሥሩ ፡ አንተን ፡ ይሸከምሃል ፡ እንጂ ፡ ሥሩን ፡ የምትሸከም ፡ አንተ ፡ አይደለህም ።

፲፱ እንግዲህ ፡— እኔ ፡ እንድገባ ፡ ቅርንጫፎች ፡ ተሰ

፳ በሩ ፡ ትል ፡ ይሆናል ። መልካም ፤ እነርሱ ፡ ካለማመን ፡ የተነሣ ፡ ተሰበሩ ፡ አንተም ፡ ከእምነት ፡ የተነሣ ፡ ቆመሃል ። ፍራ ፡ እንጂ ፡ የትዕቢትን ፡ ነገር ፡ አታስብ ።

፳፩ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ተፈጥሮት ፡ ለነበሩት ፡ ቅርንጫፎች ፡ የራራላቸው ፡ ካልሆነ ፡ ለአንተ ፡ ደግሞ ፡ አይራራልህ

፳፪ ምና ። እንግዲህ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቸርነትና ፡ ጭከና ፡ ተመልከት ፤ ጭከናው ፡ በወደቁት ፡ ላይ ፡ ነው ÷ በቸርነቱ ፡ ግን ፡ ጸንተህ ፡ ብትኖር ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ነው ፤ ያስ

፳፫ ዚያ ፡ አንተ ፡ ደግሞ ፡ ትቈረጣለህ ። እነዚያም ፡ ደግሞ ፡ ባለማመናቸው ፡ ጸንተው ፡ ባይኖሩ ፡ በዛፉ ፡ ውስጥ ፡ ይገባሉ ፤ እግዚአብሔር ፡ መልሶ ፡

፳፬ ሊያገባቸው ፡ ይችላልና ። አንተ ፡ በፍጥረቱ ፡ የበረሀ ፡ ከነበረ ፡ ወይራ ፡ ተቈርጠህ ፡ እንደ ፡ ፍጥረትህ ፡ ሳትሆን ፡ በመልካም ፡ ወይራ ፡ ከገባህ ÷ ይልቁንስ ፡ እነዚያ ፡ በፍጥረታቸው ፡ ያሉት ፡ ቅርንጫፎች ፡ በራሳቸው ፡ ወይራ ፡ እንዴት ፡ አይገቡም ?

፳፭ ወንድሞች ፡ ሆይ ÷ ልባሞች ፡ የሆናችሁ ፡ እንዳይመስላችሁ ፡ ይህን ፡ ምሥጢር ፡ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ እወዳለሁ ፤ የአሕዛብ ፡ ሙላት ፡ እስኪገባ ፡ ድረስ ፡ ድንዛዜ ፡ በእስራኤል ፡ በአንዳንድ ፡

፳፮ በኩል ፡ ሆኖባቸው ፤ እንደዚሁም ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ይድናል ፤ እንዲህ ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡—

መድኃኒት ፡ ከጽዮን ፡ ይወጣል ፡ ከያዕቆብም ፡ ኃጢአተኛነትን ፡ ያስወግዳል ።

፳፯ ኃጢአታቸውንም ፡ በወሰድላቸው ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ የምገባው ፡ ኪዳን ፡ ይህ ፡ ነው ።

፳፰ በወንጌል ፡ በኩል ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ጠላቶች ፡ ናቸው ÷ በምርጫ ፡ በኩል ፡ ግን ፡ ስለ ፡ አበቶች ፡

፳፱ ተወዳጆች ፡ ናቸው ፤ እግዚአብሔር ፡ በጸጋው ፡

፲። ፳፡ ፳፩፡ ኢሳ· ፷፭ ÷ ፩፡ ፪።

፲፩። ፩፡ ኤር· [illegible] ። ፪፡ ፩ ነገሥ· ፲፱ ÷ ፲፡ ፲፬ ። [illegible] ። ፫፡ [illegible] ። ፬፡ [illegible] ። ፭፡ [illegible] ። ፰፡ ኢሳ· [illegible] ። ፱፡ ፲፡ መዝ· ፷፰ ÷ ፳፪፡ ፳፫ ። ፲፩፡ የሐዋ· [illegible] ። ፲፮፡ ዘኍል· [illegible] ። ፲፯፡ ኤር· ፲፩ ÷ ፲፮ ። [illegible] ። [illegible] ። ፳፭፡ ኢሳ· ፶፱ ÷ ፳፡ ፳፩ ። [illegible]

፴ ስጦታና ፡ በመጥራቱ ፡ አይጸጸትምና ። እናን
ተም ፡ ቀድሞ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እንዳልታዘዛ
ችሁ ፥ አሁን ፡ ግን ፡ ከእለመታዘዛቸው ፡ የተነሣ ፡
፴፩ ምሕረት ፡ እንዳገኛችሁ ፥ እንዲሁ ፡ በተማራች
ሁበት ፡ ምሕረት ፡ እነርሱ ፡ ደግሞ ፡ ምሕረትን ፡
ያገኙ ፡ ዘንድ ፡ እነዚህ ፡ ደግሞ ፡ አሁን ፡ አልታዘ
፴፪ ዙም ። እግዚአብሔር ፡ ሁሉን ፡ ይምር ፡ ዘንድ ፡
ሁሉን ፡ በአለመታዘዝ ፡ ዘግቶታልና ።
፴፫ የእግዚአብሔር ፡ ባለ ፡ ጠግነትና ፡ ጥበብ ፡
እውቀቱም ፡ እንዴት ፡ ጥልቅ ፡ ነው ! ፍርዱ ፡
እንዴት ፡ የማይመረመር ፡ ነው ፥ ለመንገዱም ፡
ፍለጋ ፡ የለውም ።
፴፬ የጌታን ፡ ልብ ፡ ያወቀው ፡ ማን ፡ ነው ?
፴፭ ወይስ ፡ አማካሪው ፡ ማን ፡ ነበር ? ወይስ ፡
ብድራቱን ፡ ይመልስ ፡ ዘንድ ፡ ለእርሱ ፡
አስቀድሞ ፡ የሰጠው ፡ ማን ፡ ነው ?
፴፮ ሁሉ ፡ ከእርሱና ፡ በእርሱ ፡ ለእርሱም ፡ ነውና !
ለእርሱ ፡ ለዘላለም ፡ ክብር ፡ ይሁን ! አሜን ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ እንግዲህ ፥ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ሰውነታችሁን ፡
እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝና ፡ ሕያው ፡
ቅዱስም ፡ መሥዋዕት ፡ አድርጋችሁ ፡ ታቀርቡ ፡
ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ርኅራኄ ፡ እለምናች
ኋለሁ ፥ እርሱም ፡ በአእምሮ ፡ የሚመች ፡ አገል
፪ ግሎታችሁ ፡ ነው ። የእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡
እርሱም ፡ በጎና ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ፍጹምም ፡
የሆነው ፡ ነገር ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፈትናችሁ ፡
ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ በልባችሁ ፡ መታደስ ፡ ተለወጡ ፡
እንጂ ፡ ይህን ፡ ዓለም ፡ አትምሰሉ ።
፫ እግዚአብሔር ፡ ለእያንዳንዱ ፡ የእምነትን ፡
መጠን ፡ እንዳከፈለው ፥ እንደ ፡ ባለ ፡ አእምሮ ፡
እንዲያስብ ፡ እንጂ ፡ ማሰብ ፡ ከሚገባው ፡ አልፎ ፡
በትዕቢት ፡ እንዳያስብ ፡ በመካከላችሁ ፡ ላለው ፡
ለእያንዳንዱ ፡ በተሰጠኝ ፡ ጸጋ ፡ እናገራለሁ ።
፬ በአንድ ፡ አካል ፡ ብዙ ፡ ብልቶች ፡ እንዳሉን ፥
የብልቶቹም ፡ ሁሉ ፡ ሥራ ፡ አንድ ፡ እንዳይደለ ፥
፭ እንዲሁ ፡ ብዙዎች ፡ ስንሆን ፡ በክርስቶስ ፡ አንድ ፡
አካል ፡ ነን ፥ እርስ ፡ በርሳችንም ፡ እያንዳንዳችን ፡
፮ የሌላው ፡ ብልቶች ፡ ነን ። እንደ ፡ ተሰጠንም ፡
ጸጋ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ስጦታ ፡ አለን ፤ ትንቢት ፡ ቢሆን ፡
እንደ ፡ እምነታችን ፡ መጠን ፡ ትንቢት ፡ እንና
፯ ገር ፤ አገልግሎት ፡ ቢሆን ፡ በአገልግሎታችን ፡
እንትጋ ፤ የሚያስተምርም ፡ ቢሆን ፡ በማስተ
፰ ማሩ ፡ ይትጋ ፤ የሚመክርም ፡ ቢሆን ፡ በመም
ከሩ ፡ ይትጋ ፤ የሚሰጥ ፡ በልግስና ፡ ይስጥ ፤
የሚገዛ ፡ በትጋት ፡ ይግዛ ፤ የሚምር ፡ በደስታ ፡
ይማር ።
፱ ፍቅራችሁ ፡ ያለ ፡ ግብዝነት ፡ ይሁን ። ክፉ
ውን ፡ ነገር ፡ ተጸየፉት ፤ ከበጎ ፡ ነገር ፡ ጋር ፡ ተባ
፲ በሩ ፤ በወንድማማች ፡ መዋደድ ፡ እርስ ፡ በር
ሳችሁ ፡ ተዋደዱ ፤ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ተከባበሩ ፤
፲፩ ለሥራ ፡ ከመትጋት ፡ አትለግሙ ፤ በመንፈስ ፡
፲፪ የምትቃጠሉ ፡ ሁኑ ፤ ለጌታ ፡ ተገዙ ፤ በተስፋ ፡
ደስ ፡ ይበላችሁ ፤ በመከራ ፡ ታገሡ ፤ በጸሎት ፡
፲፫ ጽኑ ፤ ቅዱሳንን ፡ በሚያስፈልጋቸው ፡ እርዱ ፤
እንግዶችን ፡ ለመቀበል ፡ ትጉ ።
፲፬ የሚያሳድዱአችሁን ፡ መርቁ ፥ መርቁ ፡ እንጂ ፡
፲፭ አትርገሙ ። ደስ ፡ ከሚላቸው ፡ ጋር ፡ ደስ ፡ ይበ
፲፮ ላችሁ ፥ ከሚያለቅሱም ፡ ጋር ፡ አልቅሱ ። እርስ ፡
በርሳችሁ ፡ በአንድ ፡ አሳብ ፡ ተስማሙ ፤ የትዕ
ቢትን ፡ ነገር ፡ አታስቡ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ የትሕት
ናን ፡ ነገር ፡ ለመሥራት ፡ ትጉ ። ልባሞች ፡ የሆ
፲፯ ናችሁ ፡ አይምሰላችሁ ። ለማንም ፡ ስለ ፡ ክፉ ፡
ፈንታ ፡ ክፉን ፡ አትመልሱ ፤ በሰው ፡ ሁሉ ፡
፲፰ ፊት ፡ መልካም ፡ የሆነውን ፡ አስቡ ። ቢቻላች
ሁስ ፡ በእናንተ ፡ በኩል ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡
፲፱ በሰላም ፡ ኑሩ ። ተወዳጆች ፡ ሆይ ፥ ራሳችሁ ፡
አትበቀሉ ፥ ለቍጣው ፡ ፈንታ ፡ ስጡ ፡ እንጂ ፤
በቀል ፡ የእኔ ፡ ነው ፥ እኔ ፡ ብድራቱን ፡ እመልሳ
፳ ለሁ ፡ ይላል ፡ ጌታ ፡ ተብሎ ፡ ተጽፎአልና ። ጠላ
ትህ ፡ ግን ፡ ቢራብ ፡ አብላው ፤ ቢጠማ ፡ አጠ
ጣው ፤ ይህን ፡ በማድረግህ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ የእ
፳፩ ሳት ፡ ፍም ፡ ትከምራለህና ። ክፉውን ፡ በመል
ካም ፡ አሸንፍ ፡ እንጂ ፡ በክፉ ፡ አትሸነፍ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ ነፍስ ፡ ሁሉ ፡ በበላይ ፡ ላሉት ፡ ባለ ፡ ሥልጣኖች ፡
ይገዛ ። ከእግዚአብሔር ፡ ካልተገኘ ፡ በቀር ፡
ሥልጣን ፡ የለምና ፤ ያሉትም ፡ ባለ ፡ ሥልጣ
ኖች ፡ በእግዚአብሔር ፡ የተሾሙ ፡ ናቸው ።
፪ ስለዚህ ፡ ባለ ፡ ሥልጣንን ፡ የሚቃወም ፡ የእግ
ዚአብሔርን ፡ ሥርዓት ፡ ይቃወማል ፤ የሚቃ
ወሙትም ፡ በራሳቸው ፡ ላይ ፡ ፍርድን ፡ ይቀበ
፫ ላሉ ። ገዦዎች ፡ ለክፉ ፡ አድራጊዎች ፡ እንጂ ፡
መልካም ፡ ለሚያደርጉ ፡ የሚያስፈሩ ፡ አይደሉ
ምና ። ባለ ፡ ሥልጣንን ፡ እንዳትፈራ ፡ ትወዳለ
ህን ? መልካሙን ፡ አድርግ ፡ ከእርሱም ፡ ምስ
፬ ጋና ፡ ይሆንልሃል ፤ ለመልካም ፡ ነገር ፡ ለአንተ ፡
የእግዚአብሔር ፡ አገልጋይ ፡ ነውና ። በከንቱ ፡

፲፩ ። [illegible]

፲፪ ። [illegible]

፲፫ ። [illegible]

ግን ፡ ሰይፍ ፡ አይታጠቅምና ፡ ክፉ ፡ ብታደርግ ፡ ፍራ ፤ ቍጣውን ፡ ለማሳየት ፡ ክፉ ፡ አድራጊውን ፡ የሚበቀል ፡ የእግዚአብሔር ፡ አገልጋይ ፡ ነውና ። ፭ ስለዚህ ፡ ስለ ፡ ቍጣው ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ሕሊና ፡ ደግሞ ፡ መገዛት ፡ ግድ ፡ ነው ። ፮ ስለዚሁ ፡ ደግሞ ፡ ትገብራላችሁና ፤ በዚሁ ፡ ነገር ፡ የሚተጉ ፡ የእግዚአብሔር ፡ አገልጋዮች ፡ ናቸውና ። ፯ ለሁሉ ፡ የሚገባውን ፡ አስረክቡ ፤ ግብር ፡ ለሚገባው ፡ ግብርን ፥ ቀረጥ ፡ ለሚገባው ፡ ቀረጥን ፥ መፈራት ፡ ለሚገባው ፡ መፈራትን ፥ ክብር ፡ ለሚገባው ፡ ክብርን ፡ ስጡ ።

፰ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ከመዋደድ ፡ በቀር ፡ ለማንም ፡ ዕዳ ፡ አይኑርባችሁ ፥ ሌላውን ፡ የሚወድ ፡ ሕግን ፡ ፈጽሞታልና ። ፱ አታመንዝር ፥ አትግደል ፥ አትስረቅ ፥ በውሸት ፡ አትመስክር ፥ አትመኝ ፡ የሚለው ፡ ከሌላይቱ ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ በዚህ ፡— ባልንጀራህን ፡ እንደ ፡ ነፍስህ ፡ ውደድ ፡ በሚለው ፡ ቃል ፡ ተጠቅልሎአል ። ፲ ፍቅር ፡ ለባልንጀራው ፡ ክፉ ፡ አያደርግም ፤ ስለዚሁ ፡ ፍቅር ፡ የሕግ ፡ ፍጻሜ ፡ ነው ።

፲፩ ከእንቅልፍ ፡ የምትነሡበት ፡ ሰዓት ፡ አሁን ፡ እንደ ፡ ደረሰ ፡ ዘመኑን ፡ እወቁ ፤ ካመንንበት ፡ ጊዜ ፡ ይልቅ ፡ መዳናችን ፡ ዛሬ ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ ቀርቦአልና ። ፲፪ ሌሊቱ ፡ አልፎአል ፥ ቀኑም ፡ ቀርቦአል ። እንግዲህ ፡ የጨለማውን ፡ ሥራ ፡ አውጥተን ፡ የብርሃንን ፡ ጋሻ ፡ ጦር ፡ እንልበስ ። ፲፫ በቀን ፡ እንደምንሆን ፡ በአገባብ ፡ እንመላለስ ፤ በዘፈንና ፡ በስካር ፡ አይሁን ፥ በዝሙትና ፡ በመዳራት ፡ አይሁን ፥ በክርክርና ፡ በቅናት ፡ አይሁን ፤ ፲፬ ነገር ፡ ግን ፡ ጌታን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ ልበሱት ፤ ምኞቱንም ፡ እንዲፈጽም ፡ ለሥጋ ፡ አታስቡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ በእምነት ፡ የደከመውንም ፡ ተቀበሉት ፥ በአሳቡም ፡ ላይ ፡ አትፍረዱ ። ፪ ሁሉን ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተፈተደለት ፡ የሚያምን ፡ አለ ፥ ደካማው ፡ ግን ፡ አትክልት ፡ ይበላል ። ፫ የሚበላ ፡ የማይበላውን ፡ አይናቀው ፡ የማይበላውም ፡ በሚበላው ፡ አይፍረድ ፥ እግዚአብሔር ፡ ተቀብሎታልና ። ፬ አንተ ፡ በሌላው ፡ ሎሌ ፡ የምትፈርድ ፡ ማን ፡ ነህ ? እርሱ ፡ ቢቆም ፡ ወይም ፡ ቢወድቅ ፡ ለገዛ ፡ ጌታው ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሊያቆመው ፡ ይችላልና ፡ ይቆማል ።

፭ ይህ ፡ ሰው ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ከሌላ ፡ ቀን ፡ እንዲሻል ፡ ያስባል ፥ ያ ፡ ግን ፡ ቀን ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያስባል ፤ እያንዳንዱ ፡ በገዛ ፡ አእምሮው ፡ አጥብቆ ፡ ይረዳ ። ፮ ቀንን ፡ የሚያከብር ፡ ለጌታ ፡ ብሎ ፡ ያከብራል ፤ የሚበላም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግናልና ፡ ለጌታ ፡ ብሎ ፡ ይበላል ፤ የማይበላም ፡ ለጌታ ፡ ብሎ ፡ አይበላም ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ያመሰግናል ። ፯ ከእኛ ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ ለራሱ ፡ የሚኖር ፡ የለምና ፥ ለራሱም ፡ የሚሞት ፡ የለም ፤ ፰ በሕይወት ፡ ሆነን ፡ ብንኖር ፡ ለጌታ ፡ እንኖራለንና ፥ ብንሞትም ፡ ለጌታ ፡ እንሞታለን ። እንግዲህ ፡ በሕይወት ፡ ሆነን ፡ ብንኖር ፡ ወይም ፡ ብንሞት ፡ የጌታ ፡ ነን ። ፱ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ሙታንንም ፡ ሕያዋንንም ፡ ይገዛ ፡ ዘንድ ፡ ክርስቶስ ፡ ሞቶአልና ፡ ሕያውም ፡ ሆኖአልና ።

፲ አንተም ፡ በወንድምህ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትፈርዳለህ ? ወይስ ፡ አንተ ፡ ደግሞ ፡ ወንድምህን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትንቃለህ ? ሁላችን ፡ በክርስቶስ ፡ ፍርድ ፡ ወንበር ፡ ፊት ፡ እንቆማለንና ። ፲፩

> እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፥ ጕልበት ፡
> ሁሉ ፡ ለእኔ ፡ ይንበረከካል ፡ መላስም ፡ ሁሉ ፡
> እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግናል ፡

ተብሎ ፡ ተጽፎአልና ። ፲፪ እንግዲያስ ፡ እያንዳንዳችን ፡ ስለ ፡ ራሳችን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መልስ ፡ እንሰጣለን ።

፲፫ እንግዲህ ፡ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እርስ ፡ በርሳችን ፡ አንፈራረድ ፤ ይልቁን ፡ ግን ፡ ለወንድም ፡ እንቅፋትን ፡ ወይም ፡ ማሰናከያን ፡ ማንም ፡ እንዳያኖርበት ፡ ይህን ፡ ቍረጡ ። ፲፬ በራሱ ፡ ርኩስ ፡ የሆነ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ሌለ ፡ በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ ሆኜ ፡ አውቄአለሁ ፡ ተረድቼአለሁም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ርኩስ ፡ እንዲሆን ፡ ለሚቈጥር ፡ ለእርሱ ፡ ርኩስ ፡ ነው ። ፲፭ ወንድምህንም ፡ በመብል ፡ ምክንያት ፡ የምታሳዝን ፡ ከሆንህ ፡ እንግዲህ ፡ በፍቅር ፡ አልተመላለስህም ። ክርስቶስ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ የሞተለትን ፡ እርሱን ፡ በመብልህ ፡ አታጥፋው ። ፲፮ እንግዲህ ፡ ለእናንተ ፡ ያለው ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ አይሰደብ ፤ ፲፯ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ጽድቅና ፡ ሰላም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ የሆነ ፡ ደስታ ፡ ናት ፡ እንጂ ፡ መብልና ፡ መጠጥ ፡ አይደለችምና ። ፲፰ እንደዚህ ፡ አድርጎ ፡ ለክርስቶስ ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ ያሰኛልና ፥ ለሰውም ፡ ዘንድ ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ። ፲፱ እንግዲያስ ፡ ሰላም ፡ የሚቆምበትን ፡ እርስ ፡ በርሳችንም ፡ የምንታነጽበትን ፡ እንከተል ። ፳ በመብል ፡ ምክንያት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ አታፍርስ ። ሁሉ ፡ ንጹሕ ፡ ነው ፥ በመጠራጠር ፡ የቀበላ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ ለዚያ ፡ ሰው ፡ ክፉ ፡ ነው ። ፳፩ ሥጋን ፡ አለመብላት ፡ ወይንንም ፡ አለመጠጣት ፡ ወንድምህም ፡

፲፫ ። ፯ ፤ ማቴ· ፳፪ ፥ ፳፩ ። ፰ ፤ ማቴ· ፳፪ ፥ ፴፱ ፡ ገ ፤ ዮሐ· ፲፫ ፥ ፴፬ ። ፱ ፤ ዘፀአ· ፳ ፥ ፲፫—፲፯ ፤ ዘሌዋ· ፲፱ ፥ ፲፰ ፤ ማቴ· ፲፱ ፥ ፲፰ ፡ ፲፱ ። ፲ ፤ ፩ ቆሮ· ፲፫ ፥ ፬—፯ ፤ ገላ· ፭ ፥ ፲፬ ። ፲፩ ፤ ፩ ተሰ· ፭ ፥ ፮ ። ፲፪ ፤ ኤፌ· ፭ ፥ ፲፩ ፤ ፮ ፥ ፲፩ ። ፲፫ ፤ ሉቃ· ፳፩ ፥ ፴፬ ። ፲፬ ፤ ም· ፰ ፥ ፲፬ ፤ ገላ· ፫ ፥ ፳፯ ።

፲፬ ። ፩ ፤ ፩ ቆሮ· ፰ ፥ ፱—፲፫ ። ፪ ፤ ቄላ· ፪ ፥ ፲፮ ። ፫ ፤ ፩ ቆሮ· ፲ ፥ ፳፭ ፡ ፴፩ ። ፬ ፤ ፩ ቆሮ· ፭ ፥ ፲፪ ። ፭ ፤ ገላ· ፬ ፥ ፲ ። ፮ ፤ ፩ ተሰ· ፭ ፥ ፲ ። ፯ ፤ ማቴ· ፳፭ ፥ ፴፭ ፡ ፵፭ ። ፲፩ ፤ ኢሳ· ፵፭ ፥ ፳፫ ፤ ፊልጵ· ፪ ፥ ፲ ። ፲፫ ፤ ማቴ· ፯ ፥ ፩ ፤ ፲፰ ፥ ፯ ። ፲፬ ፤ የሐዋ· ፲ ፥ ፲፭ ፤ ቲቶ ፩ ፥ ፲፭ ። ፲፭ ፤ ፩ ቆሮ· ፰ ፥ ፲፩ ። ፲፯ ፤ ዮሐ· ፲፫ ፥ ፳፰ ። ፳ ፤ ቲ· ፲፬ ፡ ፲፭ ። ፳፩ ፤ ፩ ቆሮ· ፯ ፥ ፲፫ ።

የሚሰናከልበትን ፡ አለማድረግ ፡ መልካም ፡ ነው ።
፳፪ ለአንተ ፡ ያለህ ፡ እምነት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለራስህ ፡ ይሁንልህ ። ፈትኖ ፡ መልካም ፡ እንዲሆን ፡ በሚቈጥረው ፡ ነገር ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ የማይ
፳፫ ፈርድ ፡ ብፁዕ ፡ ነው ። የሚጠራጠረው ፡ ግን ፡ ቢበላ ፡ በእምነት ፡ ስላልሆነ ፡ ተኰንኖአል ፤ በእምነትም ፡ ያልሆነ ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአት ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ እኛም ፡ ኃይለኞች ፡ የሆንን ፡ የደካሞችን ፡ ድካም ፡ እንድንሸከም ፡ ራሳችንንም ፡ ደስ ፡ እን
፪ ዳናሰኝ ፡ ይገባናል ። እያንዳንዳችን ፡ እንድናን ጸው ፡ እርሱን ፡ ስመጥቀም ፡ ባልንጀራችንን ፡
፫ ደስ ፡ እናሰኝ ። ክርስቶስ ፡ ራሱን ፡ ደስ ፡ አላሰኘ ምና ፤ ነገር ፡ ግን ፦ አንተን ፡ የነቀፉበት ፡ ነቀፋ ፡ ወደቀብኝ ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ሆን
፬ በት ። በመጽናትና ፡ መጻሕፍት ፡ በሚሰጡት ፡ መጽናናት ፡ ተስፋ ፡ ይሆንልን ፡ ዘንድ ፡ አስቀ ድሞ ፡ የተጻፈው ፡ ሁሉ ፡ ለትምህርታችን ፡ ተጽ
፭፡፮ ፎአልና ። በአንድ ፡ ልብ ፡ ሆናችሁ ፡ በአንድ ፡ አፍ ፡ እግዚአብሔርን ፥ እርሱም ፡ የጌታችን ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አባት ፥ ታከብሩ ፡ ዘንድ ፥ የትዕግሥትና ፡ የመጽናናት ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ፈቃድ ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ በአንድ ፡ አሳብ ፡ መሆንን ፡ ይስጣችሁ ።
፯ ስለዚህ ፡ ክርስቶስ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ እንደ ፡ ተቀበላችሁ ፡ እንዲሁ ፡ እርስ ፡ በርሳ
፰፡፱ ችሁ ፡ ተቀባበሉ ። ለአባቶች ፡ የተሰጠውን ፡ የተስፋ ፡ ቃል ፡ ያጸና ፡ ዘንድ ፤ ደግሞም ፦ ስለ ዚህ ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ አመሰግንሃለሁ ፡ ለስ ምህም ፡ እዘምራለሁ ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፥ አሕዛብ ፡ ስለ ፡ ምሕረቱ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያከ ብሩ ፡ ዘንድ ፥ ክርስቶስ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ እውነት ፡ የመገረዝ ፡ አገልጋይ ፡ ሆነ ፡ እላለሁ ።
፲ ደግሞም ፦ አሕዛብ ፡ ሆይ ፥ ከሕዝቡ ፡ ጋር ፡
፲፩ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ይላል ። ደግሞም ፦

እናንተ ፡ አሕዛብ ፡ ሁላችሁ ፥ ጌታን ፡ እመ
ስግኑ ፡ ሕዝቦቹም ፡ ሁሉ ፡ ይወድሱት ፡

፲፪ ይላል ። ደግሞም ፡ ኢሳይያስ ፦

የእሴይ ፡ ሥር ፡ አሕዛብንም ፡ ሊገዛ ፡ የሚነ
ሣው ፡ ይሆናል ፤ በእርሱ ፡ አሕዛብ ፡ ተስፋ ፡
ያደርጋሉ ፡

፲፫ ይላል ። የተስፋ ፡ አምላክም ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ኃይል ፡ በተስፋ ፡ እንድትበዙ ፡ በማመናችሁ ፡ ደስታንና ፡ ሰላምን ፡ ሁሉ ፡ ይሙላባችሁ ።
፲፬ እኔም ፡ ራሴ ፡ ደግሞ ፥ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፥ በበ ጎነት ፡ ራሳችሁ ፡ እንደ ፡ ተሞላችሁ ፥ እውቀ ትም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሞላባችሁ ፥ እርስ ፡ በርስ ችሁም ፡ ደግሞ ፡ ልትገሥጹ ፡ እንዲቻላችሁ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ተረድቼአለሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ አሕ
፲፭፡፲፮ ዛብ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ተቀድሰው ፡ የተወ ደደ ፡ መሥዋዕት ፡ ሊሆኑ ፥ ስእግዚአብሔር ፡ ወንጌል ፡ እንደ ፡ ካህን ፡ እያገለገልሁ ፥ ለአሕ ዛብ ፡ የክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ አገልጋይ ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በተሰጠኝ ፡ ጸጋ ፡ ምክ ንያት ፡ ተመልሼ ፡ ላሳስባችሁ ፡ ብዬ ፡ በአንዳ ንድ ፡ በታ ፡ በድፍረት ፡ ጻፍሁላችሁ ። እንግ
፲፯ ዲህ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ በማሆን ፡ ነገር ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ትምክህት ፡ አለኝ ።
፲፰፡፲፱ አሕዛብ ፡ እንዲታዘዙ ፡ ክርስቶስ ፡ በቃልና ፡ በሥራ ፥ በምልክትና ፡ በድንቅ ፡ ነገር ፡ ኃይል ፥ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ኃይል ፡ በእኔ ፡ አድርጎ ፡ ከሠራው ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ ልናገር ፡ አልደፍርም ፤ ስለዚህ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ጀምሬ ፡ እስከ ፡ እልዋ ሪቆን ፡ ድረስ ፡ እየዞርሁ ፡ የክርስቶስን ፡ ወንጌል ፡
፳ ፈጽሜ ፡ ሰብኬአለሁ ። እንዲሁም ፡ በሌላው ፡ ሰው ፡ መሠረት ፡ ላይ ፡ እንዳልሠራ ፡ የክርስቶስ ፡ ስም ፡ በተጠራበት ፡ ስፍራ ፡ ሳይሆን ፡ ወንጌልን ፡
፳፩ ለመስበክ ፡ ተጣጣርሁ ፤ ነገር ፡ ግን ፦

ስለ ፡ እርሱ ፡ ያልተወራላቸው ፡ ያያሉ ፥
ያልሰሙም ፡ ያስተውላሉ ፡

ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ነው ።
፳፪ ስለዚህ ፡ ደግሞ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ እንዳልመጣ ፡
፳፫ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ተከለከልሁ ። አሁን ፡ ግን ፡ በዚህ ፡ አገር ፡ ስፍራ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ስለ ፡ ሌለኝ ፥ ከብዙ ፡ ዓመትም ፡ ጀምሬ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ልመጣ ፡ ናፍ
፳፬ ቆት ፡ ስላለኝ ፥ ወደ ፡ እስጳንያ ፡ በሄድሁ ፡ ጊዜ ፡ ሳልፍ ፡ እናንተን ፡ እንዳይ ፥ አስቀድሜም ፡ ጥቂት ፡ ብጠግባችሁ ፡ ወደዚያ ፡ በጕዞዬ ፡ እንድ
፳፭ ትረዱኝ ፡ ተስፋ ፡ አደርጋለሁ ። አሁን ፡ ግን ፡ ቅዱሳንን ፡ ለማገልገል ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እሄ
፳፮ ዳለሁ ። መቄዶንያና ፡ አካይያ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ቅዱሳን ፡ መካከል ፡ ያሉትን ፡ድሆች ፡ ይረዱ ፡
፳፯ ዘንድ ፡ ወደዋልና ። ወደዋልና ፥ የእነርሱም ፡ ባለ ፡ዕዳዎች ፡ ናቸው ፤ አሕዛብ ፡ በእነርሱ ፡ መን ፈሳዊ ፡ ነገርን ፡ ተካፋዮች ፡ ከሆኑ ፡ በሥጋዊ ፡ ነገር ፡ ደግሞ ፡ ያገለግሉአቸው ፡ ዘንድ ፡ ይገባቸ
፳፰ ዋልና ። እንግዲህ ፡ ይህን ፡ ፈጽሜ ፡ ይህን ፡ ፍሬ ፡ ካተምሁላቸው ፡ በኋላ ፡ በእናንተ ፡ በኩል ፡
፳፱ አልፌ ፡ ወደ ፡ እስጳንያ ፡ እሄዳለሁ ፤ ወደ ፡ እና ንተም ፡ስመጣ ፡ በክርስቶስ ፡ በረከት ፡ ሙላት ፡ እንድመጣ ፡ አውቃለሁ ።
፴ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ስለ ፡ እኔ ፡ ወደ ፡ እግዚአ ብሔር ፡ እየጸለያችሁ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ትጋደሉ ፡ ዘንድ ፡ በጌታችን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስና ፡ በመ
፴፩፡፴፪ ንፈስ ፡ ፍቅር ፡ እለምናችኋለሁ ፤ በእግዚአብ ሔር ፡ ፈቃድ ፡ በደስታ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ መጥቼ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እንዳርፍ ፥ በይሁዳ ፡ ካሉት ፡

፲፭ ። [illegible]

ከማይታዘዙ ፡ እድን ፡ ዘንድ ፥ ለኢየሩሳሌምም ፡ ያለኝ ፡ አገልግሎቴ ፡ ቅዱሳንን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ጸልዩ ። ፴፫ የሰላምም ፡ አምላክ ፡ ከሁላችሁ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፤ አሜን ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

፩ በክንክራኦስ ፡ ባለች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አገልጋይ ፡ የምትሆን ፡ እኅታችንን ፡ ፌቤንን ፡ አደራ ፡ ፪ ብያችኋለሁ ፤ ለቅዱሳን ፡ እንደሚገባ ፡ በጌታ ፡ ተቀበሉአት ፥ እርስዋ ፡ ለብዙዎች ፡ ለእኔም ፡ ለራሴ ፡ ደጋፊ ፡ ነበረችና ፥ ከእናንተም ፡ በምትፈልገው ፡ በማናቸውም ፡ ነገር ፡ እርዱአት ።

፫ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ አብረውኝ ፡ ለሚሠሩ ፡ ለጵርስቅላና ፡ ለአቂላ ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ፤ ፬ እነርሱም ፡ ስለ ፡ ነፍሴ ፡ ነፍሳቸውን ፡ ለሞት ፡ አቀረቡ ፥ የአሕዛብም ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ ሁሉ ፡ የሚያመሰግኑአቸው ፡ ናቸው ፡ እንጂ ፡ ፭ እኔ ፡ ብቻ ፡ አይደለሁም ፤ በቤታቸውም ፡ ላለች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ። ከእስያ ፡ ለክርስቶስ ፡ በኵራት ፡ ለሆነው ፡ ለምወደው ፡ ለአጤኔጦን ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ። ፮ ስለ ፡ እናንተ ፡ ብዙ ፡ ለደከመች ፡ ለማርያ ፡ ሰላ ፯ ምታ ፡ አቅርቡልኝ ። በሐዋርያት ፡ መካከል ፡ ስመ ፡ ጥሩዎች ፡ ስሆኑ ፥ ደግሞም ፡ ክርስቶስን ፡ በማመን ፡ ለቀደሙኝ ፥ አብረውኝም ፡ ለታሰሩ ፡ ለዘመዶቼ ፡ ለአንዲራኒቆንና ፡ ለዩልያን ፡ ሰላ ፰ ምታ ፡ አቅርቡልኝ ። በጌታ ፡ ለምወደው ፡ ለጵ ፱ ልያጦን ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ። በክርስቶስ ፡ አብሮን ፡ ለሚሠራ ፡ ለኢሩባኖን ፡ ለምወደውም ፡ ፲ ለስንጣክን ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ። በክርስቶስ ፡ መሆኑ ፡ ተፈትኖ ፡ ለተመሰገነው ፡ ለኤጤሌን ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ። ከአርስጣባሉ ፡ ቤተ ፡ ፲፩ ሰዎች ፡ ላሉት ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ። ለዘመዴ ፡ ለሄሮድዮና ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ። ከንርቀሱ ፡ ቤተ ፡ ሰዎች ፡ በጌታ ፡ ላሉት ፡ ሰላ ፲፪ ምታ ፡ አቅርቡልኝ ። በጌታ ፡ ሆነው ፡ ለሚደክሙ ፡ ለፕሮፊሞናና ፡ ለጢሮፊሞስ ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ። በጌታ ፡ እጅግ ፡ ለደከመች ፡ ለተወደደች ፡ ለጠርሲዳ ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ። ፲፫ በጌታ ፡ ሆኖ ፡ ለታወቀ ፡ ለሩፎን ፡ ለእኔና ፡ ለእር ፲፬ ሱም ፡ እናት ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ። ለአስቀሪጦንና ፡ ለአፍስሶንጳ ፡ ለሄሮሜንም ፡ ለጳጥሮባም ፡ ለሄርማንም ፡ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ላሉ ፡ ወንድሞች ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ። ፲፭ ለፍሌጎንና ፡ ለዩልያ ፡ ለኔርያና ፡ ለእኅቱም ፡ ለአልንጦንም ፡ ከእነርሱም ፡ ጋር ፡ ላሉ ፡ ቅዱሳን ፡ ሁሉ ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልኝ ። ፲፮ በተቀደሰ ፡ አሳሳም ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ሰላምታ ፡ ተሰጣጡ ። የክርስቶስ ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ ሁሉ ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡላችኋል ።

፲፯ ነገር ፡ ግን ፥ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ከናንተ ፡ የተማራችሁትን ፡ ትምህርት ፡ የሚቃወሙትን ፥ መለያየትንና ፡ ማሰናከያን ፡ የሚያደርጉትን ፡ ሰዎች ፡ እንድትመለከቱ ፡ እለምናችኋለሁ ፥ ከእ ፲፰ ነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ፈቀቅ ፡ በሉ ፤ እንዲህ ፡ ያሉት ፡ ለገዛ ፡ ሆዳቸው ፡ እንጂ ፡ ለጌታችን ፡ ለኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አይገዙምና ፥ በመልካምና ፡ በሚያቈላምጥ ፡ ንግግርም ፡ ተንኰል ፡ የሌለባቸውን ፡ ፲፱ ሰዎች ፡ ልብ ፡ ያታልላሉ ። መታዘዛችሁ ፡ ለሁሉ ፡ ተወርቶአልና ፤ እንግዲህ ፡ በእናንተ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለበጎ ፡ ነገር ፡ ጥበበኞች ፡ ለክፉም ፡ የዋሆች ፡ እንድትሆኑ ፡ እወዳለሁ ። ፳ የሰላምም ፡ አምላክ ፡ ሰይጣንን ፡ ከእግራችሁ ፡ በታች ፡ ፈጥኖ ፡ ይቀጠቅጠዋል ። የጌታችን ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይሁን ።

፳፩ አብሮኝ ፡ የሚሠራ ፡ ጢሞቴዎስ ፡ ዘመዶቼም ፡ ሉቂዮስና ፡ ኢያሶን ፡ ሱሲጴጥሮስም ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡላችኋል ።

፳፪ ይህን ፡ መልእክት ፡ የጻፍሁ ፡ እኔ ፡ ጤርጥዮስ ፡ በጌታ ፡ ሰላምታ ፡ አቀርብላችኋለሁ ።

፳፫ የእኔና ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሁሉ ፡ አስተናጋጅ ፡ ጋይዮስ ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርብላችኋል ። የከተማው ፡ መጋቢ ፡ ኤርስጦስ ፡ ወንድማችንም ፡ ቍአስጥሮስ ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡላችኋል ። ፳፬ የጌታችን ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋ ፡ ከሁላችሁ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፤ አሜን ።

፳፭፡፳፮ እንግዲህ ፡ እንደ ፡ ወንጌሌ ፡ ስለ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስም ፡ እንደ ፡ ተሰበከ ፥ ከዘላለም ፡ ዘመንም ፡ የተሰወረው ፡ አሁን ፡ ግን ፡ የታየው ፡ በነቢያትም ፡ መጻሕፍት ፡ የዘላለም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ አዘዘ ፡ ለእምነት ፡ መታዘዝ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ለአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ የታወቀው ፡ ምሥጢር ፡ እንደ ፡ ተገለጠ ፡ መጠን ፡ ሊያበረታችሁ ፡ ፳፯ ለሚችለው ፥ ብቻውን ፡ ጥበብ ፡ ላለው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ ክብር ፡ ይሁን ፤ አሜን ።

፲፮ ። ፫ ፤ የሐዋ. ፲፰ ፥ ፪ ። ፭ ፤ ፩ ቆሮ. ፲፮ ፥ ፲፱ ። ፲፮ ፤ ፩ ጴጥ. ፭ ፥ ፲፬ ። ፲፯ ፡ ፲፰ ፤ ፊልጵ. ፫ ፥ ፲፰ ፡ ፲፱ ፤ ቈላ. ፪ ፥ ፰ ። ፲፱ ፤ ማቴ. ፲ ፥ ፲፮ ። ፳ ፤ ዘፍጥ. ፫ ፥ ፲፭ ፤ ፩ ቆሮ. ፲፮ ፥ ፳፫ ። ፳፫ ፤ የሐዋ. ፲፱ ፥ ፳ ። ፳፫ ፤ ፩ ቆሮ. ፩ ፥ ፲፬ ፤ ፪ ጢሞ. ፬ ፥ ፳ ።

# መጀመሪያይቱ ፡ የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ቆሮንቶስ ፡ ሰዎች ።

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ በእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሐዋርያ ፡ ሊሆን ፡ የተጠራ ፡ ጳውሎስ ፡
፪ ወንድሙም ፡ ሶስቴንስ ÷ በቆሮንቶስ ፡ ላለች ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ÷ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ለተቀደሱት ÷ የእነርሱና ፡ የእኛ ፡ ጌታ ፡ የሆነውን ፡ የጌታችንን ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ ስም ፡ በየስፍራው ፡ ከሚጠሩት ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ቅዱሳን ፡ ለመሆን ፡ ለተጠሩት ፤

፫ ከእግዚአብሔር ፡ ከአባታችን ፡ ከጌታም ፡ ከኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋና ፡ ሰላም ፡ ለእናንተ ፡ ይሁን ።

፬ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ስላመናችሁ ፡ በተሰጣችሁ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ ምክንያት ፡ ሁልጊዜ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ አምላክን ፡ አመሰግናለሁ ፤
፭፡፮ ስለክርስቶስ ፡ መመስከሬ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ጸና ÷ በነገር ፡ ሁሉ ፡ በቃልም ፡ ሁሉ ፡ በእውቀትም ፡ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ ባለ ፡ ጠጎች ፡ አንድ
፯ ትሆኑ ፡ ተደርጋችኋልና ። እንደዚህ ፡ የጌታችንን ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ መገለጥ ፡ ስትጠባበቁ ፡ አንድ ፡ የጸጋ ፡ ስጦታ ፡ እንኳ ፡ አይጐድል
፰ ባችሁም ፤ እርሱም ፡ ደግሞ ፡ በጌታችን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ቀን ፡ ያለ ፡ ነቀፋ ፡ እንድትሆኑ ፡
፱ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ድረስ ፡ ያጸናችኋል ። ወደ ፡ ልጁ ፡ ወደ ፡ ጌታችን ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ኅብረት ፡ የጠራችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ የታመነ ፡ ነው ።

፲ ነገር ፡ ግን ÷ ወንድሞች ፡ ሆይ ÷ ሁላችሁ ፡ አንድ ፡ ንግግር ፡ እንድትናገሩ ፡ በአንድ ፡ ልብና ፡ በአንድ ፡ አሳብም ፡ የተባበራችሁ ፡ እንድትሆኑ ፡ እንጂ ፡ መለያየት ፡ በመካከላችሁ ፡ እንዳይሆን ፡ በጌታችን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስም ፡ እለም
፲፩ ናችኋለሁ ። ወንድሞቼ ፡ ሆይ ÷ በመካከላችሁ ፡ ክርክር ፡ እንዳለ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ የቀሎዔ ፡ ቤተ ፡
፲፪ ሰዎች ፡ አስታውቀውኛልና ። ይህንም ፡ እላለሁ ፡— እያንዳንዳችሁ ፡— እኔ ፡ የጳውሎስ ፡ ነኝ ÷ እኔስ ፡ የአጵሎስ ፡ ነኝ ÷ እኔ ፡ ግን ፡ የኬፋ ፡
፲፫ ነኝ ÷ እኔስ ፡ የክርስቶስ ፡ ነኝ ፡ ትላላችሁ ። ክርስቶስ ፡ ተከፍሎአልን ? ጳውሎስስ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ተሰቀለን ? ወይስ ፡ በጳውሎስ ፡ ስም ፡
፲፬፡፲፭ ተጠመቃችሁን ? በስሜ ፡ እንደ ፡ ተጠመቃችሁ ፡ ማንም ፡ እንዳይል ፡ ከቀርስጶስና ፡ ከጋይዮስ ፡ በቀር ፡ ከእናንተ ፡ አንድን ፡ እንኳ ፡ ስላጠመቅሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግናለሁ ።
፲፮ የእስጢፋናስንም ፡ ቤተ ፡ ሰዎች ፡ ደግሞ ፡ አጠምቄአለሁ ፤ ጨምሬ ፡ ሌላ ፡ አጥምቄ ፡ እንደ ፡
፲፯ ሆነ ፡ አላውቅም ። ለማጥመቅ ፡ ክርስቶስ ፡ አላከኝምና ÷ ወንጌልን ፡ ልሰብክ ፡ እንጂ ፤ የክርስቶስ ፡ መስቀል ፡ ከንቱ ፡ እንዳይሆን ፡ በቃል ፡ ጥበብ ፡ አይደለም ።

፲፰ የመስቀሉ ፡ ቃል ፡ ለሚጠፉት ፡ ሞኝነት ÷ ለእኛ ፡ ለምንድን ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ኃይል ፡
፲፱ ነውና ። የጥበበኞችን ፡ ጥበብ ፡ አጠፋለሁ ፡ የአስተዋዮችንም ፡ ማስተዋል ፡ እጥላለሁ ፡ ተብሎ ፡
፳ ተጽፎአልና ። ጥበበኛ ፡ የት ፡ አለ ? ጻፊስ ፡ የት ፡ አለ ? የዚች ፡ ዓለም ፡ መርማሪስ ፡ የት ፡ አለ ? እግዚአብሔር ፡ የዚችን ፡ ዓለም ፡ ጥበብ ፡
፳፩ ሞኝነት ፡ እንዲሆን ፡ አላደረገምን ? በእግዚአብሔር ፡ ጥበብ ፡ ምክንያት ፡ ዓለም ፡ እግዚአብሔርን ፡ በጥበብዋ ፡ ስላላወቀች ÷ በስብከት ፡ ሞኝነት ፡ የሚያምኑትን ፡ ሊያድን ፡ የእግዚአብሔር ፡
፳፪ በጎ ፡ ፈቃድ ፡ ሆኖአልና ። መቼም ፡ አይሁድ ፡ ምልክትን ፡ ይለምናሉ ፡ የግሪክ ፡ ሰዎችም ፡ ጥበ
፳፫ ብን ፡ ይሻሉ ፤ እኛ ፡ ግን ፡ የተሰቀለውን ፡ ክርስቶስን ፡ እንሰብካለን ፤ ይህም ፡ ለአይሁድ ፡ ማሰ
፳፬ ናከያ ፡ ለአሕዛብም ፡ ሞኝነት ፡ ነው ÷ ለተጠሩት ፡ ግን ÷ አይሁድ ፡ ቢሆኑ ፡ የግሪክ ፡ ሰዎችም ፡ ቢሆኑ ÷ የእግዚአብሔር ፡ ኃይልና ፡ የእግዚአብሔር ፡
፳፭ ጥበብ ፡ የሆነው ፡ ክርስቶስ ፡ ነው ። ከሰው ፡ ይልቅ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሞኝነት ፡ ይጠበባልና ÷ የእግዚአብሔርም ፡ ድካም ፡ ከሰው ፡ ይልቅ ፡ ይበረታልና ።

፳፮ ወንድሞች ፡ ሆይ ÷ መጠራታችሁን ፡ ተመልከቱ ፤ እንደ ፡ ሰው ፡ ጥበብ ፡ ጥበበኞች ፡ የሆኑ ፡ ብዙዎች ÷ ኀያላን ፡ የሆኑ ፡ ብዙዎች ÷ ባላባ
፳፯ ቶች ፡ የሆኑ ፡ ብዙዎች ፡ አልተጠሩም ። ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ጥበበኞችን ፡ እንዲያሳፍር ፡ የዓለምን ፡ ሞኝ ፡ ነገር ፡ መረጠ ፤ ብርቱንም ፡ ነገር ፡ እንዲያሳፍር ፡ እግዚአብሔር ፡ የዓ
፳፰ ለምን ፡ ደካማ ፡ ነገር ፡ መረጠ ፤ እግዚአብሔርም ፡ የሆነውን ፡ ነገር ፡ እንዲያጠፋ ፡ የዓለምን ፡ ምናምንቴ ፡ ነገር ፡ የተናቀውንም ፡ ነገር ፡ ያል
፳፱ ሆነውንም ፡ ነገር ፡ መረጠ ÷ ሥጋን ፡ የለበሰ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንዳይመካ ።
፴፡፴፩ ነገር ፡ ግን ፡— የሚመካ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ይመካ ፡

፩። ፪፣፫፤ ሮሜ ፩፥፯። ፬፤ ፊልጵ. ፩፥፫። ፰፤ ፩ተሰ. ፭፥፳፫፤ ፩ዮሐ. ፩፥፫። ፲፤ ፊልጵ. ፪፥፪፣፫። ፲፪፤ የሐዋ. ፲፰፥፳፬፤ ዮሐ. ፩፥፵፪። ፲፫፤ የሐዋ. ፲፰፥፰። ፲፬፤ የሐዋ. ፲፱፥፳፱፤ ሮሜ ፲፮፥፳፫። ፲፯፤ ሮሜ ፩፥፲፮። ፲፱፤ ኢሳ. ፳፱፥፲፬። ፳፤ ኢሳ. ፴፫፥፲፰፤ ሮሜ ፩፥፳፪። ፳፩፤ ማቴ. ፲፩፥፳፭። ፳፪፤ ማቴ. ፲፪፥፴፰፤ ዮሐ. ፬፥፵፰፤ የሐዋ. ፲፯፥፲፰። ፳፫፤ ገላ. ፭፥፲፩። ፳፬፤ ቆላ. ፪፥፫። ፳፮፤ ዮሐ. ፯፥፵፰። ፳፯፤ ያዕ. ፪፥፭። ፳፰፤ ሮሜ ፬፥፲፯። ፴፤ ዮሐ. ፲፯፥፲፱፤ ፪ቆሮ. ፭፥፳፩። ፴፩፤ ኤር. ፱፥፳፫፣፳፬።

ተብሎ፡እንደ፡ተጻፈው፡ይሆን፡ዘንድ ÷ ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ጥበብና፡ጽድቅ፡ቅድስናም፡ቤዛነትም፡በተደረገልን፡በክርስቶስ፡ኢየሱስ፡የሆናችሁ፡ከእርሱ፡ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ እኔም ÷ ወንድሞች፡ሆይ ÷ ወደ፡እናንተ፡በመጣሁ፡ጊዜ፡በቃልና፡በጥበብ፡ብልጫ፡ለእግዚአብሔር፡ምስክርነቴን፡ለእናንተ፡እየ ፪ ነገርሁ፡አልመጣሁም ። በመካከላችሁ፡ሳለሁ፡ከኢየሱስ፡ክርስቶስ፡በቀር፡እርሱም፡እንደ፡ተሰቀለ፡ሌላ፡ነገር፡እንዳላውቅ፡ቍርጬ፡ነበ ፫ ርና ። እኔም፡በድካምና፡በፍርሃት፡በብዙ፡መንቀጥቀጥም፡በእናንተ፡ዘንድ፡ነበርሁ ፤ ፬፡፭ እምነታችሁም፡በእግዚአብሔር፡ኃይል፡እንጂ፡በሰው፡ጥበብ፡እንዳይሆን ÷ ቃሌም፡ስብከቴም፡መንፈስንና፡ኃይልን፡በመግለጥ፡ነበረ፡እንጂ ÷ በሚያባብል፡በጥበብ፡ቃል፡አልነበረም ።

፮ በሰሰሉት፡ መካከል፡ግን፡ጥበብን፡እንናገራለን ÷ ነገር፡ግን፡የዚችን፡ዓለም፡ጥበብ፡አይደለም፡የሚሻሩትንም፡የዚችን፡ዓለም፡ ፯ ገዦች፡ጥበብ፡አይደለም ፤ ነገር፡ግን፡እግዚአብሔር፡አስቀድሞ፡ከዘመናት፡በፊት፡ለክብራችን፡የወሰነውን ÷ ተሰውሮም፡የነበረውን፡የእግዚአብሔርን፡ጥበብ፡በምሥጢር፡እንና ፰ ገራለን ። ከዚችም፡ዓለም፡ገዦች፡አንዱ፡እንኳ፡ይህን፡ጥበብ፡አላወቀም ፤ አውቀውስ፡ቢሆኑ፡የክብርን፡ጌታ፡ባልሰቀሉትም፡ነበር ፤ ፱ ነገር፡ግን — ዓይን፡ያላየችው፡ጆሮም፡ያልሰማው፡በሰውም፡ልብ፡ያልታሰበው፡እግዚአብሔር፡ለሚወዱት፡ያዘጋጀው፡ተብሎ፡ ፲ እንደ፡ተጻፈ ÷ እንዲህ፡እንናገራለን ። መንፈስም፡የእግዚአብሔርን፡ጥልቅ፡ነገር፡ስንኳ፡ሳይቀር፡ሁሉን፡ይመረምራልና፡ለእኛ፡እግዚአብሔር፡በመንፈሱ፡በኩል፡ገለጠው ። ፲፩ በእርሱ፡ውስጥ፡ካለው፡ከሰው፡መንፈስ፡በቀር፡ለሰው፡ያለውን፡የሚያውቅ፡ሰው፡ማን፡ነው ? እንዲሁም፡ደግሞ፡ከእግዚአብሔር፡መንፈስ፡በቀር፡ለእግዚአብሔር፡ያለውን፡ ፲፪ ማንም፡አያውቅም ። እኛ፡ግን፡ከእግዚአብሔር፡እንዲያው፡የተሰጠንን፡እናውቅ፡ዘንድ፡ከእግዚአብሔር፡የሆነውን፡መንፈስ፡እንጂ፡ ፲፫ የዓለምን፡መንፈስ፡አልተቀበልንም ። መንፈሳዊውን፡ነገር፡ከመንፈሳዊው፡ነገር፡ጋር፡አስተያይተን፡መንፈስ፡በሚያስተምረን፡ቃል፡ይህን፡ደግሞ፡እንናገራለን፡እንጂ፡የሰው፡ጥበብ፡በሚያስተምረን፡ቃል፡አይደለም ።

፲፬ ለፍጥረታዊ፡ሰው፡የእግዚአብሔር፡መንፈስ፡ነገር፡ሞኝነት፡ነውና፡አይቀበለውም ፤ በመንፈስም፡የሚመረመር፡ስለ፡ሆነ፡ሊያውቀው፡አይችልም ። ፲፭ መንፈሳዊ፡ሰው፡ግን፡ሁሉን፡ይመረምራል፡ራሱ፡ግን፡በማንም፡አይመረመርም ። ፲፮ እንዲያስተምረው፡የጌታን፡ልብ፡ማን፡አውቆት፡ነው ? እኛ፡ግን፡የክርስቶስ፡ልብ፡አለን ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ እኔም ÷ ወንድሞች፡ሆይ ÷ የሥጋ፡እንደ፡መሆናችሁ ÷ በክርስቶስም፡ሕፃናት፡እንደ፡መሆናችሁ፡እንጂ፡መንፈሳውያን፡እንደ፡መሆናችሁ፡ልናገራችሁ፡አልቻልሁም ። ፪ ገና፡ጽኑ፡መብል፡ለመብላት፡አትችሉም፡ነበርና፡ወተት፡ጋትኋችሁ ፤ ፫ ገና፡ሥጋውያን፡ናችሁና፡እስከ፡አሁን፡ድረስ፡ገና፡አትችሉም ። ቅናትና፡ክርክር፡ስለሚገኝባችሁ፡ሥጋውያን፡መሆናችሁ፡አይደላችሁምን ? እንደ፡ሰው፡ልማድስ፡አትመላለሱምን ? ፬ አንዱ — እኔ፡የጳውሎስ፡ነኝ ÷ ሁለተኛውም — እኔ፡የአጵሎስ፡ነኝ፡ቢል፡ሰዎች፡ብቻ፡መሆናችሁ፡አይደለምን ?

፭ አጵሎስ፡እንግዲህ፡ምንድር፡ነው ? ጳውሎስስ፡ምንድር፡ነው ? በእነርሱ፡እጅ፡ያመናችሁ፡አገልጋዮች፡ናቸው ፤ ለእያንዳንዳቸውም፡ጌታ፡እንደ፡ሰጣቸው፡ያገለግላሉ ። ፮ እኔ፡ተከልሁ፡አጵሎስም፡አጠጣ፡ነገር፡ግን፡ ፯ እግዚአብሔር፡ያሳድግ፡ነበር ፤ እንግዲያስ፡የሚያሳድግ፡እግዚአብሔር፡እንጂ፡የሚተክል፡ቢሆን፡ወይም፡የሚያጠጣ፡ቢሆን፡አን ፰ ዳች፡አይደለም ። የሚተክልና፡የሚያጠጣ፡አንድ፡ናቸው ÷ ነገር፡ግን፡እያንዳንዱ፡እንደ፡ራሱ፡ድካም፡መጠን፡የራሱን፡ደመወዝ፡ይቀ ፱ በላል ። የእግዚአብሔር፡እርሻ፡ናችሁ ፤ የእግዚአብሔር፡ሕንፃ፡ናችሁ ፤ ከእርሱ፡ጋር፡አብረን፡የምንሠራ፡ነንና ።

፲ የእግዚአብሔር፡ጸጋ፡እንደ፡ተሰጠኝ፡መጠን፡እንደ፡ብልሃተኛ፡የአናጺ፡አለቃ፡መሠረትን፡መሠረትሁ ÷ ሌላውም፡በላዩ፡ያንጻል ። እያንዳንዱ፡ግን፡በእርሱ፡ላይ፡እንዴት፡እንዲያንጽ፡ይጠንቀቅ ። ፲፩ ከተመሠረተው፡በቀር፡ማንም፡ሌላ፡መሠረት፡ሊመሠርት፡አይችልምና ÷ እርሱም፡ኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ነው ። ፲፪ ማንም፡ግን፡በዚህ፡መሠረት፡ላይ፡በወርቅ፡ቢሆን፡በብርም፡በክቡር፡ድንጋይም፡በእንጨትም፡በሣርም፡ወይም፡በአገዳ፡ቢያንጽ ÷ ፲፫ የእያንዳንዱ፡ሥራ፡ይገለጣል ፤

፪ ። ፩፡ ምዕ. ፩፥ ፲፯ ። ፪፡ ገላ. ፮፥ ፲፬ ። ፫፡ የሐዋ. ፲፰፥ ፩፤፪ ቆሮ. ፲፥ ፩ ። ፬፡ ሮሜ ፲፭፥ ፲፱፤፩ ተሰ. ፩፥ ፭ ። ፮፡ ፪ ቆሮ. ፱፥ ፯ ። ፯፡ ሮሜ ፲፮፥ ፳፭፤፳፮፤ቆላ. ፩፥ ፳፯ ። ፰፡ መዝ. ፳፫፥ ፯–፲፤ሉቃ. ፳፬፥ ፳ ። ፱፡ ኢሳ. ፷፬፥ ፬ ። ፲፡ ማቴ. ፲፫፥ ፲፩፤ኤፌ. ፫፥ ፫፤፭ ። ፲፩፡ ሮሜ ፰፥ ፲፮ ። ፲፫፡ የሐ. ፲፱፥ ፳፯ ። ፲፮፡ ኢሳ. ፵፥ ፲፫፤ሮሜ ፲፩፥ ፴፬፤የሐ. ፲፭፥ ፲፭ ።

፫ ። ፪፡ ዕብ. ፭፥ ፲፪፤፲፫ ። ፫፡ ምዕ. ፩፥ ፲፩፤፲፩፥ ፲፰ ። ፬፡ ምዕ. ፩፥ ፲፪ ። ፭፡ የሐዋ. ፲፰፥ ፳፬፤፳፯ ። ፮፡ ማር. ፬፥ ፳፮ ። ፱–፲፩፡ ኤፌ. ፪፥ ፳፤፳፪፤፩ ጴጥ. ፪፥ ፬–፮ ። ፲፫፡ ሚል. ፫፥ ፪፤፫፤ ፩ ተሰ. ፩፥ ፯፥ ፰ ።

በእሳት፡ስለሚገለጥ፡ያ፡ቀን፡ያስያልና፥የእ ያንዳንዱም፡ሥራ፡እንዴት፡መሆኑን፡እሳቱ፡ ፲፬ ይፈትነዋል ። ማንም፡በእርሱ፡ላይ፡ያነጸው፡ ፲፭ ሥራ፡ቢጸናለት፡ደመወዙን፡ይቀበላል ፤ የማ ንም፡ሥራ፡የተቃጠለበት፡ቢሆን፡ይጐዳበ ታል፥እርሱ፡ራሱ፡ግን፡ይድናል፡ነገር፡ግን፡ በእሳት፡እንደሚድን፡ይሆናል ።

፲፮ የእግዚአብሔር፡ቤተ፡መቅደስ፡እንደ፡ሆና ችሁ፡የእግዚአብሔርም፡መንፈስ፡እንዲኖር ፲፯ ባችሁ፡አታውቁምን ? ማንም፡የእግዚአብሔ ርን፡ቤተ፡መቅደስ፡ቢያፈርስ፡እግዚአብሔር፡ እርሱን፡ያፈርሰዋል ፤ የእግዚአብሔር፡ቤተ፡ መቅደስ፡ቅዱስ፡ነውና፥ያውም፡እናንተ፡ ናችሁ ።

፲፰ ማንም፡ራሱን፡አያታልል ፤ ከእናንተ፡ ማንም፡በዚች፡ዓለም፡ጥበበኛ፡የሆነ፡ቢመ ስለው፡ጥበበኛ፡ይሆን፡ዘንድ፡ሞኝ፡ይሁን ። ፲፱ የዚች፡ዓለም፡ጥበብ፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡ ሞኝነት፡ነውና ። እርሱ፡ጥበበኞችን፡በተን ኰላቸው፡የሚይዝ ፤ ደግሞም ፦ ጌታ፡የጥ በበኞችን፡አሳብ፡ከንቱ፡እንደ፡ሆነ፡ያውቃል፡ ፳ ተብሎ፡ተጽፎአልና ። ስለዚህም፡ማንም፡ ፳፩ በሰው፡አይመካ ። ነገር፡ሁሉ፡የእናንተ፡ነውና ፤ ፳፪ ጳውሎስ፡ቢሆን፡አጵሎስም፡ቢሆን፡ኬፋም፡ ቢሆን፡ዓለምም፡ቢሆን፡ሕይወትም፡ቢሆን፡ ሞትም፡ቢሆን፡ያለውም፡ቢሆን፡የሚመጣ ፳፫ ውም፡ቢሆን፥ሁሉ፡የእናንተ፡ነው ፥ እናን ተም፡የክርስቶስ፡ናችሁ፡ክርስቶስም፡የእግ ዚአብሔር፡ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ እንዲሁ፡ሰው፡እኛን፡እንደ፡ክርስቶስ፡ሎሌ ዎችና፡እንደ፡እግዚአብሔር፡ምሥጢር፡መጋ ፪ ቢዎች፡ይቍጠረን ። እንደዚህም፡ሲሆን፥ በመጋቢዎች፡ዘንድ፡የታመነ፡ሆኖ፡መገኘት፡ ፫ ይፈለጋል ። ነገር፡ግን፡በእናንተ፡ዘንድ፡ ወይም፡በሌላ፡ሰው፡ዘንድ፡ብፈረድ፡ለእኔ፡ ምንም፡አይደለም ፤ እኔም፡በራሴ፡እንኳ፡ ፬ አልፈርድም ፤ በራሴ፡ላይ፡ምንም፡አላውቅ ምና፥ነገር፡ግን፡በዚህ፡አልጸድቅም ፤ እኔን፡ ፭ የሚፈርድ፡ግን፡ጌታ፡ነው ። ስለዚህም፡በጨ ለማ፡የተሰወረውን፡ደግሞ፡ወደ፡ብርሃን፡ የሚያወጣ፡የልብንም፡ምክር፡የሚገልጥ፡ ጌታ፡እስኪመጣ፡ድረስ፡ጊዜው፡ሳይደርስ፡ አንዳች፡አትፍረዱ ፤ በዚያን፡ጊዜም፡ለእያ ንዳንዱ፡ምስጋናው፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ ይሆናል ።

፮ ወንድሞች፡ሆይ፥ስለ፡አንዱ፡በአንዱ፡ላይ፡ እንዳትታበዩ፡እንዳይታበዩ፦ ከተጻፈው፡አት ለፍ፡የሚለውን፡በእኛ፡ትማሩ፡ዘንድ፥ይህን፡ በእናንተ፡ምክንያት፡ስለ፡ራሴና፡ስለ፡አጵ ፯ ሎስ፡እንደ፡ምሳሌ፡ተናገርሁ ። አንተ፡እን ድትበልጥ፡ማን፡አድርጎሃል ? ያልተቀበልኸ ውስ፡ምን፡አለህ ? የተቀበልህ፡ከሆንህ፡ግን፡ እንዳልተቀበልህ፡የምትመካ፡ስለ፡ምንድር፡ ነው ?

፰ አሁን፡ጠግባችኋል ፤ አሁንስ፡ባለ፡ጠጎች፡ ሆናችኋል ፤ ያለ፡እኛ፡ነግሣችኋል ! እኛ፡ ደግሞ፡ከእናንተ፡ጋር፡እንድንነግሥ፡ብትነ ፱ ግሡ፡መልካም፡ይሆን፡ነበር ። ለዓለም፡ለመ ላእክትም፡ለሰዎችም፡መጫወቻ፡ሆነናልና ፤ እግዚአብሔር፡እኛን፡ሐዋርያቱን፡ሞት፡እንደ፡ ተፈረደባቸው፡ሰዎች፡ከሁሉ፡ይልቅ፡የኋለ ፲ ኞች፡እንዳደረገን፡ይመስለኛልና ። እኛ፡ስለ፡ ክርስቶስ፡ሞኞች፡ነን፡እናንተ፡ግን፡በክርስ ቶስ፡ልባሞች፡ናችሁ ፤ እኛ፡ደካሞች፡ነን፡ እናንተ፡ግን፡ኀይለኞች፡ናችሁ ፤ እናንተ፡ የከበራችሁ፡ናችሁ፡እኛ፡ግን፡የተዋረድን፡ ፲፩ ነን ። እስከዚህ፡ሰዓት፡ድረስ፡እንራባለን፥ እንጠማለን፥እንራቆታለን፥እንጐሰማለን፥ ፲፪ እንከራተታለን፥በገዛ፡እጃችን፡እየሠራን፡ እንደክማለን ፤ ሲሰድቡን፡እንመርቃለን፥ሲያ ፲፫ ሳድዱን፡እንታገሣለን፥ከፉ፡ሲናገሩን፡እንማ ልዳለን ፤ እስከ፡አሁን፡ድረስ፡የዓለም፡ጥራጊ፡ የሁሉም፡ጕድፍ፡ሆነናል ።

፲፬ እንደምወዳችሁ፡ልጆቼ፡አድርጌ፡ልገሥጻ ችሁ፡እንጂ፡ላሳፍራችሁ፡ይህን፡አልጽፍም ። ፲፭ በክርስቶስ፡አእላፍ ፡ሞግዚቶች፡ቢኖሩአ ችሁ፡ብዙ፡አባቶች፡የሉአችሁም ፤ እኔ፡በክር ስቶስ፡ኢየሱስ፡በወንጌል፡ወልጄአችኋለሁና ። ፲፮ እንግዲህ፡እኔን፡የምትመስሉ፡ሁኑ፡ብዬ፡ ፲፯ እለምናችኋለሁ ። ስለዚህ፡የምወደውንና፡የታ መነውን፡በጌታ፡ልጄ፡የሆነውን፡ጢሞቴዎ ስን፡ልኬላችኋለሁ፥እኔም፡በየስፍራው፡በአ ብያተ፡ክርስቲያናት፡ሁሉ፡እንደማስተምር፡ በክርስቶስ፡ኢየሱስ፡የሚሆነውን፡መንገዴን፡ ፲፰ እርሱ፡ያሳስባችኋል ። እንዳንዶች፡ግን፡ወደ፡ እናንተ፡የማልመጣ፡እየመሰላቸው፡የታበዩ፡ ፲፱ አሉ ፤ ነገር፡ግን፡ጌታ፡ቢፈቅድ፡ፈጥኜ፡ ወደ፡እናንተ፡እመጣለሁ፥የትዕቢተኞችንም፡ ኀይል፡አውቃለሁ፡እንጂ፡ቃላቸውን፡አይደ ፳ ለም ፤ የእግዚአብሔር፡መንግሥት፡በኀይል፡ ፳፩ ነው፡እንጂ፡በቃል፡አይደለምና ። ምን፡ትወ ዳላችሁ ? በበትር፡ወይስ፡በፍቅርና፡በየዋ ሃት፡መንፈስ፡ልምጣባችሁ ?

፫ ። ፲፯ [illegible] ። ፲፱ [illegible] ። ፳ [illegible] ። ፳፩ [illegible] ።

፬ ። [illegible]

ምዕራፍ፡፭ ።

፩ በአጭር፡ቃል፡በእናንተ፡መካከል፡ዝሙት፡እንዳለ፡ይወራል፡የዚያም፡ዓይነት፡ዝሙት፡በአሕዛብስ፡እንኳ፡የማይገኝ፡ነው፥የአባቱን፡ ፪ ሚስት፡ያገባ፡ሰው፡ይኖራልና ። እናንተም፡ታብያችኋል ፤ ይልቅስ፡እንድታዝኑ፡አይገባችሁምን ? ይህን፡ሥራ፡የሠራው፡ከመካከላችሁ፡ይወገድ ።

፫፡፬ እኔ፡ምንም፡እንኳ፡በሥጋ፡ከእናንተ፡ጋር፡ባልሆን፥በመንፈስ፡ከእናንተ፡ጋር፡ነኝ፥ከእናንተም፡ጋር፡እንዳለሁ፡ሆኜ፡ይህን፡እንደዚህ፡በሠራው፡ላይ፡በጌታችን፡በኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ስም፡አሁን፡ፈርጀበታለሁ ፤ እናንተና፡መንፈሴም፡ከጌታችን፡ከኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ ፭ ኃይል፡ጋር፡ተሰብስበን፥መንፈሱ፡በጌታ፡በኢየሱስ፡ቀን፡ትድን፡ዘንድ፡እንደዚህ፡ያለው፡ለሥጋው፡ጥፋት፡ለሰይጣን፡እንዲሰጥ፡ፍርዴ፡ነው ።

፮ መመኪያችሁ፡መልካም፡አይደለም ። ጥቂት፡እርሾ፡ሊጡን፡ሁሉ፡እንዲያቦካ፡አታውቁ ፯ ምን ? እንግዲህ፡ያለ፡እርሾ፡እንዳላችሁ፡አዲሱን፡ሊጥ፡ትሆኑ፡ዘንድ፡አሮጌውን፡እርሾ፡አስወግዱ ። ፋሲካችን፡ክርስቶስ፡ታርዶአ ፰ ልና ፤ ስለዚህ፡በቅንነትና፡በእውነት፡ቂጣ፡በዓልን፡እናድርግ፡እንጂ፡በአሮጌ፡እርሾ፡በክፋትና፡በግፍ፡እርሾም፡አይደለም ።

፱ ከሴሰኞች፡ጋር፡እንዳትተባበሩ፡በመልእ ፲ ክቱ፡ጻፍሁላችሁ ። በጠቅላላው፡የዚህን፡ዓለም፡ሴሰኞችን፥ወይም፡ገንዘብን፡የሚመኙትን፡ነጣቂዎችንም፥ወይም፡ጣዖትን፡የሚያመልኩትን፡አላልሁም ፤ ይህስ፡ቢሆን፡ከዓ ፲፩ ለም፡ልትወጡ፡ይገባችሁ፡ነበር ። አሁን፡ግን፡ወንድሞች፡ከሚባሉት፡አንዱ፡ሴሰኛ፡ወይም፡ገንዘብን፡የሚመኝ፡ወይም፡ጣዖትን፡የሚያመልክ፡ወይም፡ተሳዳቢ፡ወይም፡ሰካር፡ወይም፡ነጣቂ፡ቢሆን፡ከእርሱ፡ጋር፡እንዳትተባበሩ፡እጽፍላችኋለሁ ፤ እንደነዚህ፡ካለው፡ጋር፡ ፲፪ መብል፡እንኳን፡አትብሉ ። በውጭ፡ባሉ፡ሰዎች፡ላይ፡መፍረድ፡ምን፡አግዶኝ ? በውስጥ፡ባሉ፡ሰዎች፡ላይ፡እናንተ፡አትፈርዱ ፲፫ ምን ? በውጭ፡በሉቱ፡ግን፡እግዚአብሔር፡ይፈርድባቸዋል ። ክፉውን፡ከመካከላችሁ፡አውጡት ።

ምዕራፍ፡፮ ።

፩ ከእናንተ፡አንዱ፡ከባልንጀራው፡ጋር፡ሙግት፡ቢኖረው፡በቅዱሳን፡ፊት፡በመፋረድ፡ፋንታ፡በዓመፀኞች፡ፊት፡ሊፋረድ፡ይደፍራ ፪ ልን ? ቅዱሳን፡በዓለም፡ላይ፡እንዲፈርዱ፡አታውቁምን ? በዓለምስ፡ላይ፡ብትፈርዱ፡ከሁሉ፡ይልቅ፡ትንሽ፡ስለሚሆን፡ነገር፡ልትፈርዱ፡ ፫ አትበቁምን ? የትዳር፡ጉዳይ፡ይቅርና፡በመላእክት፡እንኳ፡እንድንፈርድ፡አታውቁምን ? ፬ እንግዲህ፡ስለ፡ትዳር፡ጉዳይ፡የፍርድ፡ቤት፡ቢያስፈልጋችሁ፡በቤተ፡ክርስቲያን፡የተናቁትን፡ሰዎች፡ፈራጆች፡አድርጋችሁ፡ታበቀ ፭ ምጣላችሁን ? አሳፍራችሁ፡ዘንድ፡ይህን፡እላለሁ ። እንደዚህ፡ነውን ? በወንድሞች፡መካከል፡ሽማግሌ፡ሊሆን፡የሚችል፡አንድ፡ልባም፡ሰው፡በእናንተ፡ዘንድ፡አይገኝ ፮ ምን ? ነገር፡ግን፡ወንድም፡ወንድሙን፡ይከስል፥ይህም፡በማያምኑ፡ፊት፡ይደረጋልን ?

፯ እንግዲህ፡ፈጽሞ፡የእርስ፡በርስ፡ሙግት፡እንዳለባችሁ፡በእናንተ፡ጉድለት፡ነው ። ብትበደሉ፡አይሻልምን ? ብትታለሉስ፡አይሻልምን ? ፰ ነገር፡ግን፡እናንተ፡ትበድላላችሁ፡ታታልሉ ማላችሁ፥ያውም፡ወንድሞቻችሁን ።

፱ ወይስ፡ዓመፀኞች፡የእግዚአብሔርን፡መንግሥት፡እንዳይወርሱ፡አታውቁምን ? አትሳቱ ፤ ሴሰኞች፡ቢሆኑ፡ወይም፡ጣዖትን፡የሚያመልኩ፡ወይም፡አመንዝሮች፡ወይም፡ቀላጮች፡ወይም፡ከወንድ፡ጋር፡ዝሙት፡የሚ ፲ ሠሩ፡ወይም፡ሌቦች፡ወይም፡ገንዘብን፡የሚመኙ፡ወይም፡ሰካሮች፡ወይም፡ተሳዳቢዎች፡ወይም፡ነጣቂዎች፡የእግዚአብሔርን፡መንግ ፲፩ ሥት፡አይወርሱም ። ከእናንተም፡አንዳንዶቹ፡እንደ፡እነዚህ፡ነበራችሁ ፤ ነገር፡ግን፡በጌታ፡በኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ስም፡በአምላካችንም፡መንፈስ፡ታጥባችኋል፥ተቀድሳችኋል፥ጸድቃችኋል ።

፲፪ ሁሉ፡ተፈቅዶልኛል፥ሁሉ፡ግን፡አይጠቅምም ። ሁሉ፡ተፈቅዶልኛል፥በእኔ፡ላይ፡ግን፡አንድ፡ነገር፡እንኳ፡አይሠለጥንብኝም ። ፲፫ መብል፡ለሆድ፡ነው፥ሆድም፡ለመብል፡ነው ፤ እግዚአብሔር፡ግን፡ይህንም፡ያንም፡ያጠፋቸዋል ። ሥጋ፡ግን፡ለጌታ፡ነው፡እንጂ፡ለዝሙት፡አይደለም ፤ ጌታም፡ለሥጋ፡ነው ፤ ፲፬ እግዚአብሔርም፡ጌታንም፡አስነሣ፡እኛንም፡ ፲፭ በኃይሉ፡ያስነሣናል ። ሥጋችሁ፡የክርስቶስ፡ብልቶች፡እንደ፡ሆነ፡አታውቁምን ? እንግዲህ፡የክርስቶስን፡ብልቶች፡ወስጄ፡የጋለሞታ፡ብልቶች፡ላድርጋቸውን ? አይገባም ። ፲፮ ወይስ፡ከጋለሞታ፡ጋር፡የሚተባበር፡አንድ፡ሥጋ፡እንዲሆን፡አታውቁምን ? ሁለቱ፡አንድ፡ሥጋ፡ ፲፯ ይሆናሉ፡ተብሎአልና ። ከጌታ፡ጋር፡የሚተ ፲፰ ባበር፡ግን፡አንድ፡መንፈስ፡ነው ። ከዝሙት፡ሽሹ ። ሰው፡የሚያደርገው፡ኃጢአት፡ሁሉ፡ከሥጋ፡ውጭ፡ነው ፤ ዝሙትን፡የሚሠራ፡

፭ ። ፩ ፤ ዘሌዋ. ፲፰፥፰ ። ፫ ፤ ቆላ. ፪፥፭ ። ፬ ፤ ፪ ቆሮ. ፲፫፥፲ ። ፭ ፤ ፩ ጢሞ. ፩፥፳ ። ፮ ፤ ማቴ. ፲፫፥፴፫ ፤ ገላ. ፭፥፱ ። ፯ ፤ ዘፀአ. ፲፪፥፫—፭ ። ፰ ፤ ዘፀአ. ፲፪፥፲፭—፳ ፤ ማቴ. ፲፮፥፮ ፥ ፲፪ ። ፲ ፤ ዮሐ. ፲፯፥፲፭ ፤ ሮሜ. ፲፯፥፲፰ ። ፲፩ ፤ ፪ ተሰ. ፫፥፮ ። ፲፫ ፤ ዘዳግ. ፲፯፥፯ ።

፮ ። ፩ ፤ ማቴ. ፲፰፥፲፯ ። ፪ ፤ ማቴ. ፭፥፳፰ ፥ ፱ ። ፱ ፥ ፲ ፤ ገላ. ፭፥፲፱—፳፩ ። ፲፩ ፤ ቲቶ ፫፥፫—፯ ። ፲፪ ፤ ሮሜ. ፲፬፥፲፬ ፥ ፳፯ ፥ ፳፫ ። ፲፭ ፤ ኤፌ. ፭፥፴ ። ፲፮ ፤ ዘፍጥ. ፪፥፳፬ ። ፲፯ ፤ ዮሐ. ፲፯፥፳፩—፳፫ ።

ግን ፡ በግዛ ፡ ሥጋው ፡ ላይ ፡ ኃጢአትን ፡ ይሠራል ። ፲፱፡ ወይስ ፡ ሥጋችሁ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የተቀበላችሁት ፡ በእናንተ ፡ የሚኖረው ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አታውቁምን ? በዋጋ ፡ ተገዝታችኋልና ፡ ለራሳችሁ ፡ አይደላችሁም ፤ ስለዚህ ፡ በሥጋችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አክብሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩፤ ስለ ፡ ጻፋችሁልኝስ ፡ ነገር ፥ ከሴት ፡ ጋር ፡ አለመገናኘት ፡ ለሰው ፡ መልካም ፡ ነው ። ፪፤ ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ዝሙት ፡ ጠንቅ ፡ ለእያንዳንዱ ፡ ለራሱ ፡ ሚስት ፡ ትኑረው ፡ ለእያንዳንዲቱ ፡ ደግሞ ፡ ለራሰዋ ፡ ባል ፡ ይኑራት ። ፫፤ ባል ፡ ለሚስቱ ፡ የሚገባትን ፡ ያድርግላት ፥ እንደዚሁም ፡ ደግሞ ፡ ሚስቲቱ ፡ ለበልዋ ። ፬፤ ሚስት ፡ በገዛ ፡ ሥጋዋ ፡ ላይ ፡ ሥልጣን ፡ የላትም ፥ ሥልጣን ፡ ለበልዋ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ ባል ፡ በገዛ ፡ ሥጋው ፡ ላይ ፡ ሥልጣን ፡ የለውም ፥ ሥልጣን ፡ ለሚስቱ ፡ ነው ፡ እንጂ ። ፭፤ ለጸሎት ፡ ትተጉ ፡ ዘንድ ፡ ተስማምታችሁ ፡ ለጊዜው ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፥ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ አትከላከሉ ፤ ራሳችሁን ፡ ስለ ፡ አለመግዛት ፡ ሰይጣን ፡ እንዳይፈታተናችሁ ፡ ደግሞ ፡ አብራችሁ ፡ ሁኑ ። ፮፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ ይህን ፡ እንደ ፡ ፈቃድ ፡ እላለሁ ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ ትእዛዝ ፡ አይደለም ። ፯፤ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ እኔ ፡ ሊሆን ፡ እወዳለሁና ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እያንዳንዱ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ለራሱ ፡ የጸጋ ፡ ስጦታ ፡ አለው ፥ አንዱ ፡ እንደዚህ ፡ ሁለተኛውም ፡ እንደዚያ ።

፰፤ ላላገቡና ፡ ለመበለቶች ፡ ግን ፡ እላለሁ ፡— እንደ ፡ እኔ ፡ ቢኖሩ ፡ ለእነርሱ ፡ መልካም ፡ ነው ፤ ፱፤ ነገር ፡ ግን ፡ በምኞት ፡ ከመቃጠል ፡ መጋባት ፡ ይሻላልና ፡ ራሳቸውን ፡ መግዛት ፡ ባይችሉ ፡ ያግቡ ።

፲፤ ሚስትም ፡ ከበልዋ ፡ አትለያይ ፥ ብትለያይ ፡ ግን ፡ ሳታገባ ፡ ትኑር ፡ ወይም ፡ ከባልዋ ፡ ትታረቅ ፥ ባልም ፡ ሚስቱን ፡ አይተዋት ፡ ብዬ ፡ የተጋቡትን ፡ አዛቸዋለሁ ፥ እኔ ፡ ግን ፡ አላዝም ፥ ጌታ ፡ እንጂ ።

፲፪፤ ሌሎችንም ፡ እኔ ፡ እላለሁ ፥ ጌታም ፡ አይደለም ፤ ከወንድሞች ፡ ወገን ፡ ያላመነች ፡ ሚስት ፡ ያለችው ፡ ቢኖር ፡ እርስዋም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ልትቀመጥ ፡ ብትስማማ ፥ አይተዋት ፤ ፲፫፤ ያላመነ ፡ ባል ፡ ያላት ፡ ሚስትም ፡ ብትኖር ፡ ይህ ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ ሊቀመጥ ፡ ቢስማማ ፥ አትተወው ። ፲፬፤ ያላመነ ፡ ባል ፡ በሚስቱ ፡ ተቀድሶአልና ፥ ያላመነችም ፡ ሚስት ፡ በበልዋ ፡ ተቀድሳለች ፤ አለዚያ ፡ ልጆቻችሁ ፡ ርኩሳን ፡ ናቸው ፤ አሁን ፡ ግን ፡ የተቀደሱ ፡ ናቸው ። ፲፭፤ የማያምን ፡ ግን ፡ ቢለይ ፡ ይለይ ፤ ወንድም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ እኅት ፡ እንዲህ ፡ ስሚመስል ፡ ነገር ፡ አይገዙም ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በሰላም ፡ ጠርቶናል ። ፲፮፤ አንቺ ፡ ሴት ፥ ባልሽን ፡ ታድኚ ፡ እንደ ፡ ሆንሽ ፡ ምን ፡ ታውቂአለሽ ? ወይስ ፥ አንተ ፡ ሰው ፥ ሚስትህን ፡ ታድን ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ ምን ፡ ታውቃለህ ?

፲፯፤ ብቻ ፡ ለእያንዳንዱ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ከፈለለት ፡ እያንዳንዱንም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ጠራው ፡ እንዲሁ ፡ ይመላለስ ። እንዲሁም ፡ በአብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ ሁሉ ፡ እደነግጋለሁ ። ፲፰፤ ማንም ፡ ተገርዞ ፡ ሳለ ፡ ተጠርቶ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ ወደ ፡ አለመገረዝ ፡ አይመለስ ፤ ማንም ፡ ሳይገረዝ ፡ ተጠርቶ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አይገረዝ ። ፲፱፤ መገረዝ ፡ ቢሆን ፡ አለመገረዝም ፡ ቢሆን ፡ ከንቱ ፡ ነው ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ መጠበቅ ፡ ነው ፡ እንጂ ። ፳፤ እያንዳንዱ ፡ በተጠራበት ፡ መጠራት ፡ እንደዚሁ ፡ ይኑር ። ፳፩፤ ባሪያ ፡ ሆነህ ፡ ተጠርተህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አይገድህም ፤ አርነት ፡ ልትወጣ ፡ ቢቻልህ ፡ ግን ፡ አርነትን ፡ ተቀበል ። ፳፪፤ ባሪያ ፡ ሆኖ ፡ በጌታ ፡ የተጠራ ፡ የጌታ ፡ ነጻ ፡ ነውና ፤ እንዲሁም ፡ ነጻ ፡ ሆኖ ፡ የተጠራ ፡ የክርስቶስ ፡ ባሪያ ፡ ነው ። ፳፫፤ በዋጋ ፡ ተገዝታችኋል ፤ የሰው ፡ ባሪያዎች ፡ አትሁኑ ። ፳፬፤ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ እያንዳንዱ ፡ በተጠራበት ፡ እንደዚሁ ፡ ሆኖ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ይኑር ።

፳፭፤ ስለ ፡ ደናግልም ፡ የጌታ ፡ ትእዛዝ ፡ የለኝም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ የታመንሁ ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ ከጌታ ፡ ምሕረትን ፡ የተቀበልሁ ፡ እንደ ፡ መሆኔ ፡ ምክር ፡ እመክራለሁ ። ፳፮፤ እንግዲህ ፡ ስለ ፡ አሁኑ ፡ ችግር ፡ ይህ ፡ መልካም ፡ ይመስለኛል ፤ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ሆኖ ፡ ቢኖር ፡ መልካም ፡ ነው ። ፳፯፤ በሚስት ፡ ታስረህ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ መፈታትን ፡ አትሻ ፤ በሚስት ፡ አልታሰርህ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ ሚስትን ፡ አትሻ ። ፳፰፤ ብታገባ ፡ ግን ፡ ኃጢአት ፡ አትሠራም ፤ ድንግሊቱም ፡ ብታገባ ፡ ኃጢአት ፡ አትሠራም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ በሚያደርጉ ፡ በሥጋቸው ፡ ላይ ፡ መከራ ፡ ይሆንባቸዋል ፥ እኔም ፡ እራራላችሁ ፡ ነበር ። ፳፱፤ ዳሩ ፡ ግን ፥ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ እናገራለሁ ፤ ዘመኑ ፡ አጭር ፡ ሆኖአል ፤ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ሚስቶች ፡ ያሉአቸው ፡ እንደሌላቸው ፡ ይሁኑ ፥ ፴፤ የሚያለቅሱም ፡ እንደ ፡ ማያለቅሱ ፥ ደስ ፡ የሚላቸውም ፡ ደስ ፡ እንደማይላቸው ፥ የሚገዙም ፡ ምንም ፡ እንደሌላቸው ፥ ፴፩፤ በዚችም ፡ ዓለም ፡ የሚጠቀሙ ፡ በሙሉ ፡ እንደ ፡ ማይጠቀሙበት ፡ ይሁኑ ፤ የዚች ፡ ዓለም ፡ መልክ ፡ አላፊ ፡ ነውና ።

፴፪፤ ነገር ፡ ግን ፡ ያለ ፡ አሳብ ፡ ልትኖሩ ፡ እወዳለሁ ። ያላገበው ፡ ጌታን ፡ እንዴት ፡ ደስ ፡ እንዲያሰኘው ፡ የጌታን ፡ ነገር ፡ ያስባል ፤ ፴፫፤ ያገባው ፡ ግን ፡ ሚስቱን ፡ እንዴት ፡ ደስ ፡ እንዲያሰኛት ፡ የዓለምን ፡ ነገር ፡ ያስባል ፥ ልቡም ፡ ተከፍሎአል ። ፴፬፤ ያልተ

[illegible footnotes]

ጋባች ፡ ሴትና ፡ ድንግል ፡ በሥጋም ፡ በነፍስም ፡ እንዲቀደሱ ፡ የጌታን ፡ ነገር ፡ ያስባሉ ፤ የተጋ ባች ፡ ግን ፡ ባልዋን ፡ እንዴት ፡ ደስ ፡ እንድታሰ ኘው ፡ የዓለምን ፡ ነገር ፡ ታስባለች ። ፴፭ ይህንም ፡ ስለራሳችሁ ፡ ጥቅም ፡ እላለሁ ፤ በአገባብ ፡ እንድ ትኖሩ ፡ ሳትባክኑም ፡ በጌታ ፡ እንድትጸኑ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ላጠምዳችሁ ፡ ብዬ ፡ አይደለም ።

፴፮ ዳሩ ፡ ግን ፡ ማግባት ፡ ወደሚገባው ፡ ዕድሜ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ ድንግልናው ፡ ያፈረ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፥ የወደደውን ፡ ያድርግ ፤ ኃጢአት ፡ የለበ ትም ፤ ይጋቡ ። ፴፯ ሳይናወጥ ፡ በልቡ ፡ የጸና ፡ ግን ፡ ግድ ፡ የሰበትም ፥ የወደደውን ፡ እንዲያደ ርግ ፡ ተፈቅዶለታል ፤ ድንግልናውንም ፡ በልቡ ፡ ይጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ቢጸና ፥ መልከም ፡ አደረገ ። ፴፰ እንዲሁም ፡ ድንግልን ፡ ያገባ ፡ መልካም ፡ አደ ረገ ፡ ያላገባም ፡ የተሻለ ፡ አደረገ ።

፴፱ ሴት ፡ ባልዋ ፡ በሕይወት ፡ ሳለ ፡ የታሰረች ፡ ናት ፤ ባልዋ ፡ ቢሞት ፡ ግን ፡ በጌታ ፡ ይሁን ፡ እንጂ ፡ የወደደችውን ፡ ልታገባ ፡ ነፃነት ፡ አላት ። ፵ እንደ ፡ ምክሬ ፡ ግን ፡ እንዳለች ፡ ብትኖር ፡ ደስ ተኛ ፡ ናት ፤ እኔም ፡ ደግሞ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ በእኔ ፡ ያለ ፡ ይመስለኛል ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ ለጣዖት ፡ ስለ ፡ ተሠዋ ፡ ሥጋም ፥ ሁላችን ፡ እውቀት ፡ እንዳለን ፡ እናውቃለን ። እውቀት ፡ ፪ ያስታብያል ፡ ፍቅር ፡ ግን ፡ ያንጻል ። ማንም ፡ አንዳች ፡ የሚያውቅ ፡ ቢመስለው ፡ ሊያውቅ ፡ ፫ እንደሚገባው ፡ ገና ፡ አላወቀም ፤ ማንም ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ቢወድ ፡ እርሱ ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ የታወቀ ፡ ነው ።

፬ እንግዲህ ፡ ለጣዖት ፡ የተሠዋውን ፡ ሥጋ ፡ ስለ ፡ መብላት ፥ ጣዖት ፡ ሁሉ ፡ በዓለም ፡ ከንቱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከአንዱም ፡ በቀር ፡ ማንም ፡ አም ፭ ላክ ፡ እንደሌለ ፡ እናውቃለን ። መቼም ፡ ብዙ ፡ አማልክትና ፡ ብዙ ፡ ጌቶች ፡ አሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በሰማይ ፡ ሆነ ፡ በምድርም ፡ ሆነ ፡ አማልክት ፡ ፮ የተባሉ ፡ ምንም ፡ ቢኖሩ ፥ ለእኛስ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ የሆነ ፡ እኛም ፡ ለእርሱ ፡ የሆንን ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ አብ ፡ አለን ፥ ነገር ፡ ሁሉም ፡ በእርሱ ፡ በኩል ፡ የሆነ ፡ እኛም ፡ በእርሱ ፡ በኩል ፡ የሆ ንን ፡ አንድ ፡ ጌታ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አለን ።

፯ ነገር ፡ ግን ፡ ይህ ፡ እውቀት ፡ በሁሉ ፡ ዘንድ ፡ አይገኝም ፤ አንዳንዶች ፡ ግን ፡ ጣዖትን ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ ድረስ ፡ ስለ ፡ ስመዱ ፡ — ለጣዖት ፡ የተ ሠዋ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ይበላሉና ፡ ሕሊናቸው ፡ ፰ ደካማ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ይረክሳል ። መብል ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አያቀርበንም ፤ ብንበላም ፡ ምንም ፡ አይጐድለንም ፡ ብንበላም ፡ ምንም ፡ አይተርፈንም ። ፱ ዳሩ ፡ ግን ፡ ይህ ፡ መብታችሁ ፡ ለደካሞች ፡ ዕንቅፋት ፡ እንዳይሆንባቸው ፡ ተጠ ንቀቁ ። ፲ አንተ ፡ እውቀት ፡ ያለህ ፡ በጣዖት ፡ ቤት ፡ በማዕድ ፡ ለትቀመጥ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ቢያ ይህ ፥ ደካማ ፡ ሰው ፡ ቢሆን ፡ ለጣዖት ፡ የተሠዋ ውን ፡ ለመብላት ፡ ሕሊናው ፡ አይታነጽበትምን ? ፲፩ በአንተ ፡ እውቀትም ፡ ይህ ፡ ደካማ ፡ ይጠፋል ፥ እርሱም ፡ ክርስቶስ ፡ የሞተለት ፡ ወንድም ፡ ነው ። ፲፪ እንዲህም ፡ ወንድሞችን ፡ እየበደላችሁ ፡ ደከ ማም ፡ የሆነውን ፡ ሕሊናቸውን ፡ እያቈሰላችሁ ፡ ክርስቶስን ፡ ትበድላላችሁ ። ፲፫ ስለዚህም ፡ መብል ፡ ወንድሜን ፡ የሚያሰናክለው ፡ ከሆነ ፥ ወንድ ሜን ፡ እንዳላሰናክለው ፡ ለዘላለም ፡ ከቶ ፡ ሥጋ ፡ አልበላም ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ እኔ ፡ ነጻ ፡ አይደለሁምን ? ሐዋርያስ ፡ አይደለ ሁምን ? ጌታችንን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስንስ ፡ አላ የሁትምን ? እናንተስ ፡ በጌታ ፡ ሥራዬ ፡ አይደ ፪ ላችሁምን ? የሐዋርያነቴ ፡ ማኅተም ፡ በጌታ ፡ እናንተ ፡ ናችሁና ፡ ለሌሎች ፡ ሐዋርያ ፡ ባልሆን ፡ ለእናንተስ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ሐዋርያ ፡ ነኝ ።

፫ ለሚመረምሩኝ ፡ መልሴ ፡ ይህ ፡ ነው ። ፬ ልን በላና ፡ ልንጠጣ ፡ መብት ፡ የለንምን ? ፭ እንደ ፡ ሌሎቹ ፡ ሐዋርያትና ፡ እንደ ፡ ጌታ ፡ ወንድሞች ፡ እንደ ፡ ኬፋም ፥ እኅት ፡ ሚስታችንን ፡ ይዘን ፡ ልንዞር ፡ መብት ፡ የለንምን ? ፮ ወይስ ፡ ሥራን ፡ ለመተው ፡ መብት ፡ የሌለን ፡ እኔና ፡ በርናባስ ፡ ብቻ ፡ ነን ? ፯ ከቶ ፡ በገዛ ፡ ገንዘቡ ፡ በወታደርነት ፡ የሚያገለግል ፡ ማን ፡ ነው ? ወይስ ፡ ወይን ፡ ተክሎ ፡ ፍሬውን ፡ የማይበላ ፡ ማን ፡ ነው ? ወይስ ፡ መንጋ ፡ እየጠበቀ ፡ ከመንጋው ፡ ወተት ፡ የማይ ጠጣ ፡ ማን ፡ ነው ?

፰ ይህን ፡ በሰው ፡ ሥልጣን ፡ ብቻ ፡ እላለሁን ? ፱ ሕግስ ፡ ደግሞ ፡ ያን ፡ አይልምን ? የሚያበራየ ውን ፡ በሬ ፡ አፉን ፡ አትሰር ፡ ተብሎ ፡ በሙሴ ፡ ሕግ ፡ ተጽፎአልና ። እግዚአብሔርስ ፡ ስለ ፡ በሬ ዎች ፡ ይገደዋልን ? ፲ ይህን ፡ የሚለው ፡ ፈጽሞ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ አይደለምን ? የሚያርስ ፡ በተስፋ ፡ ሊያርስ ፡ የሚያበራይም ፡ እንዲከፈል ፡ በተስፋ ፡ ሊያበራይ ፡ ስለሚገባው ፡ በእውነት ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ ተጽፎአል ። ፲፩ እኛ ፡ መንፈሳዊን ፡ ነገር ፡ የዘራን ላችሁ ፡ ከሆንን ፡ የእናንተን ፡ የሥጋዊን ፡ ነገር ፡ እኛ ፡ ብናጭድ ፡ ትልቅ ፡ ነገር ፡ ነውን ? ፲፪ ሌሎች ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ይህን ፡ መብት ፡ የሚካፈሉ ፡

---

፯። ፴፱ ፤ ሮሜ ፯ ፥ ፪ ።

፰። ፩ ፤ የሐዋ ፲፭ ፥ ፳፱ ። ፬ ፤ ሥራ ፫ ፥ ፲፯ ፤ ፲፫ ፥ ፲፱ ። ፬ ፤ ዘዳግ ፬ ፥ ፴፱ ። ፮ ፤ ሚል ፪ ፥ ፲ ፤ ቈላ ፩ ፥ ፲፮ ። ፯ ፤ ሮሜ ፲፬ ፥ ፲፬ ፤ ፳፫ ። ፰ ፤ ሮሜ ፲፬ ፥ ፲፯ ። ፱ ፤ ሮሜ ፲፬ ፥ ፲፫ ፤ ገላ ፭ ፥ ፲፫ ። ፲፩ ፤ ሮሜ ፲፬ ፥ ፲፭ ። ፲፪ ፤ ማቴ ፳፭ ፥ ፵ ። ፲፫ ፤ ሮሜ ፲፬ ፥ ፳፩ ።

፱። ፩ ፤ ሥራ ፲፭ ፥ ፲፯ ፤ የሐዋ ፱ ፥ ፫—፮ ፤ ፳፮ ፤ ፪ ቆሮ ፲፪ ፥ ፲፩ ፡ ፲፪ ። ፪ ፤ ፪ ቆሮ ፫ ፥ ፩—፫ ። ፬ ፤ ማቴ ፲ ፥ ፲ ። ፭ ፤ ማቴ ፲፫ ፥ ፶፭ ፤ ፰ ፥ ፲፬ ። ፱ ፤ ዘዳግ ፳፭ ፥ ፬ ። ፲ ፤ ሮሜ ፬ ፥ ፳፫ ፤ ፳፬ ፤ ፪ ጢሞ ፪ ፥ ፯ ። ፲፩ ፤ ሮሜ ፲፭ ፥ ፳፯ ። ፲፪ ፤ ፪ ቆሮ ፲፩ ፥ ፱ ፤ ፯ ፥ ፫ ።

ከሆኑ፡ እኛማ፡ ይልቁን፡ እንዴታ ?
ነገር፡ ግን፡ የክርስቶስን፡ ወንጌል፡ እንዳንከለክል፡ በሁሉ፡ እንታገሣለን፡ እንጂ፡ በዚህ፡
፲፫፤ መብት፡ አልተጠቀምንም ። በመቅደስ፡ ነገር፡ የሚያገለግሉ፡ ከመቅደስ፡ የሆነውን፡ ነገርን፡ እንዲመገቡ፥ በመሠዊያውም፡ የሚጸኑ፡ ከመ
፲፬፤ ሠዊያው፡ እንዲካፈሉ፡ አታውቁምን ? እንዲሁ፡ ደግሞ፡ ወንጌልን፡ የሚሰብኩ፡ ከወንጌል፡ ቀለብ፡ እንዲቀበሉ፡ ጌታ፡ ደንግጎአል ።
፲፭፤ እኔ፡ ግን፡ ከእነዚህ፡ ሁሉ፡ ምንም፡ አልተጠቀምሁም ። እንዲሁ፡ እንዲሆንልኝ፡ ይህን፡ አልጽፍም ፤ ማንም፡ ትምክህቴን፡ ከንቱ፡ ከሚያ
፲፮፤ ደርግብኝ፡ ሞት፡ ይሻለኛልና ። ወንጌልን፡ ብሰብክ፡ እንኳ፡ የምመካበት፡ የለኝም ፤ ግድ፡ ደርሶብኝ፡ ነውና ፤ ወንጌልንም፡ ባልሰብክ፡ ወዮ
፲፯፤ ልኝ ። ይህን፡ በፈቃዴ፡ ባደርገው፡ ደመወዝ፡ አለኝና ፤ ያለ፡ ፈቃዴ፡ ግን፡ ባደርገው፡ መጋ
፲፰፤ ቢነት፡ በአደራ፡ ተሰጥቶኛል ። እንግዲህ፡ ደመወዜ፡ ምንድር፡ ነው ? ወንጌልን፡ እየሰበክሁ፡ በወንጌል፡ ካለኝ፡ መብት፡ በሙሉ፡ እንዳልጠቀም፡ ወንጌልን፡ ያለ፡ ዋጋ፡ ብናገር፡ ነው ።
፲፱፤ ከሰው፡ ሁሉ፡ አርነት፡ የወጣሁ፡ ስሆን፡ የሚበልጡትን፡ እንድጠቅም፡ እንደ፡ ባሪያ፡ ራሴን፡
፳፤ ለሁሉ፡ አስገዛለሁ ። አይሁድንም፡ እጠቅም፡ ዘንድ፡ ከአይሁድ፡ ጋር፡ እንደ፡ አይሁዳዊ፡ ሆንሁ ፤ ከሕግ፡ በታች፡ ያሉትን፡ እጠቅም፡ ዘንድ፥ እኔ፡ ራሴ፡ ከሕግ፡ በታች፡ ሳልሆን፥ ከሕግ፡ በታች፡ ላሉት፡ ከሕግ፡ በታች፡ እንዳ
፳፩፤ ለሁ፡ ሆንሁ ፤ ሕግ፡ የሌላቸውን፡ እጠቅም፡ ዘንድ፥ ያለ፡ እግዚአብሔር፡ ሕግ፡ ሳልኖር፡ ነገር፡ ግን፡ በክርስቶስ፡ ሕግ፡ በታች፡ ሳለሁ፥ ሕግ፡ ለሌላቸው፡ ሕግ፡ እንደ፡ ሌለኝ፡ ሆንሁ ፤
፳፪፤ ደካሞችን፡ እጠቅም፡ ዘንድ፡ ለደካሞች፡ እንደ፡ ደካማ፡ ሆንሁ ፤ በሁሉ፡ መንገድ፡ አንዳንዶችን፡ አድን፡ ዘንድ፥ ከሁሉ፡ ጋር፡ በሁሉ፡ ነገር፡
፳፫፤ እንደ፡ እነርሱ፡ ሆንሁ ። በወንጌልም፡ ማኅበረተኛ፡ እሆን፡ ዘንድ፡ ስለ፡ ወንጌል፡ ሁሉን፡ አደርጋለሁ ።
፳፬፤ በእሽቅድምድም፡ ስፍራ፡ የሚሮጡት፥ ሁሉ፡ እንዲሮጡ፡ ነገር፡ ግን፡ አንዱ፡ ብቻ፡ ዋጋውን፡ እንዲቀበል፡ አታውቁምን ? እንዲ
፳፭፤ ሁም፡ ታገኙ፡ ዘንድ፡ ሩጡ ። የሚታገልም፡ ሁሉ፡ በነገር፡ ሁሉ፡ ሰውነቱን፡ ይገዛል ፤ እነዚያም፡ የሚጠፋውን፡ አክሊል፡ ሊያገኙ፡ ነው፥
፳፮፤ እኛ፡ ግን፡ የማይጠፋውን ። ስለዚህ፡ እኔ፡ ያለ፡ አሳብ፡ እንደሚሮጥ፡ ሁሉ፡ እንዲሁ፡ አልሮጥም፥ ነፋስን፡ እንደሚጎስም፡ ሁሉ፡ እን
፳፯፤ ዲሁ፡ አልጋደልም ፤ ነገር፡ ግን፡ ለሌሎች፡ ከሰበክሁ፡ በኋላ፡ ራሴ፡ የተጣልሁ፡ እንዳልሆን፡ ሥጋዬን፡ እየጎሰምሁ፡ አስገዛዋለሁ ።

## ምዕራፍ፡ ፲ ።

፩፤ ወንድሞች፡ ሆይ፥ ይህን፡ታውቁ፡ዘንድ፡እወዳለሁ ። አባቶቻችን፡ ሁሉ፡ ከደመና፡ በታች፡ ነበሩ፡ ሁሉም፡ በባሕር፡ መካከል፡ ተሻገሩ ፤
፪፤ ሁሉም፡ ሙሴን፡ ይተባበሩ፡ ዘንድ፡ በደመናና፡
፫፤ በባሕር፡ ተጠመቁ ፤ ሁሉም፡ ያን፡ መንፈሳዊ፡
፬፤ መብል፡ በሉ፥ ሁሉም፡ ያን፡ መንፈሳዊ፡ መጠጥ፡ ጠጡ ፤ ይከተላቸው፡ ከነበረው፡ ከመንፈሳዊ፡ ዓለት፡ ጠጥተዋልና፥ ያም፡ ዓለት፡ ክርስቶስ፡ ነበረ ።
፭፤ እግዚአብሔር፡ ግን፡ ከእነርሱ፡ በሚበዙት፡ ደስ፡ አላለውም፥ በምድረ፡ በዳ፡ ወድቀዋልና ።
፮፤ እነዚህም፡ ከፉ፡ ነገር፡ እንደ፡ ተመኙ፡ እኛ፡
፯፤ ደግሞ፡ እንዳንመኝ፡ ይህ፡ ምሳሌ፡ ሆነልን ። ሕዝብም፡ ሊበሉ፡ ሊጠጡም፡ ተቀመጡ፡ ሊዘፍኑም፡ ተነሡ፡ ተብሎ፡ እንደ፡ ተጻፈ፡ ከእነርሱ፡ አንዳንዶቹ፡ እንዳደረጉት፡ ጣዖትን፡ የምታመልኩ፡ አትሁኑ ።
፰፤ ከእነርሱም፡ አንዳንዶቹ፡ እንደ፡ ሴሰኑ፡ በአንድ፡ ቀንም፡ ሁለት፡ እልፍ፡ ከሦስት፡ ሺህ፡ እንደ፡ ወደቁ፡ አንሴስን ።
፱፤ ከእነርሱም፡ አንዳንዶቹ፡ ጌታን፡ እንደ፡ ተፈታተኑት፡ በእባቦቹም፡ እንደ፡ ጠፉ፡ ጌታን፡ አንፈ
፲፤ ታተን ። ከእነርሱም፡ አንዳንዶቹ፡ እንዳንጎራጎሩ፡ በሚያጠፋውም፡ እንደ፡ ጠፉ፡ አታንጐርጕሩ ።
፲፩፤ ይህም፡ ሁሉ፡ እንደ፡ ምሳሌ፡ ሆነባቸው፥ እኛንም፡ የዘመናት፡ መጨረሻ፡ የደረሰብንን፡ ሊገሥጸን፡ ተጻፈ ።
፲፪፤ ስለዚህ፡ እንደ፡ ቆመ፡ የሚመስለው፡ እንዳይወድቅ፡ ይጠንቀቅ ።
፲፫፤ ለሰው፡ ሁሉ፡ ከሚሆነው፡ በቀር፡ ምንም፡ ፈተና፡ አልደረሰባችሁም ፤ ነገር፡ ግን፡ ከሚቻላችሁ፡ መጠን፡ ይልቅ፡ ትፈተኑ፡ ዘንድ፡ የማይፈቅድ፡ እግዚአብሔር፡ የታመነ፡ ነው፥ ትታገሡም፡ ዘንድ፡ እንድትችሉ፡ ከፈተናው፡ ጋር፡ መውጫውን፡ ደግሞ፡ ያደርግላችኋል ።
፲፬፤ በለዚህ፥ ወዳጆቼ፡ ሆይ፥ ጣዖትን፡ ከማምለክ፡ ሽሹ ።
፲፭፤ ልባሞች፡ እንደ፡ መሆናችሁ፡ እላለሁ ፤ በምለው፡ ነገር፡ እናንተ፡ ፍረዱ ።
፲፮፤ የምንባርከው፡ የበረከት፡ ጽዋ፡ ከክርስቶስ፡ ደም፡ ጋር፡ ኅብረት፡ ያለው፡ አይደለምን ? የምንቈርሰውስ፡ እንጀራ፡ ከክርስቶስ፡ ሥጋ፡
፲፯፤ ጋር፡ ኅብረት፡ ያለው፡ አይደለምን ? አንድ፡ እንጀራ፡ ስለ፡ ሆነ፥ እኛ፡ ብዙዎች፡ ስንሆን፡ አንድ፡ ሥጋ፡ ነን ፤ ሁላችን፡ ያን፡ አንዱን፡

፱። ፲፫፤ ዘኍ. ፲፰፥፰። ፲፬፤ ሉቃ. ፲፥፯። ፲፭፤ ሐዋ. ፳፥፴፬። ፲፮፤ ሮሜ. ፩፥፲፬፤ ገላ. ፪፥፯። ፲፰፤ ማቴ. ፳፥፳፮፡፳፯። ፳፤ የሐዋ. ፲፮፥፫፤ ፳፩—፳፮። ፳፩፤ ገላ. ፪፥፫። ፳፪፤ ፪ ቆሮ. ፲፩፥፳፱። ፳፬፤ ዕብ. ፲፪፥፩። ፳፭፤ ፩ ጴጥ. ፭፥፬። ፳፯፤ ሮሜ ፰፥፲፫።

፲። ፩፤ ዘፀ. ፲፫፥፳፩፤ ፲፬፥፳፪። ፪፤ ዘፀ. ፲፬፥፳፪፡፳፱፤ የሐዋ. ፯፥፴፮። ፫፤ ዘፀ. ፲፮፥፲፭። ፬፤ ዘፀ. ፲፯፥፮፤ ዘኍ. ፳፥፲፩። ፭፤ ዘኍ. ፲፬፥፴፪—፴፯። ፮፤ ዘኍ. ፲፩፥፬። ፯፤ ዘፀ. ፴፪፥፮። ፰፤ ዘኍ. ፳፭፥፩፡፱። ፱፤ ዘኍ ፳፩፥፭፡፮። ፲፤ ዘኍ. ፲፬፥፴፯፤ ፲፮፥፵፱። ፲፩፤ ሮሜ ፲፭፥፬። ፲፪፤ ሮሜ. ፲፩፥፳። ፲፫፤ ፩ ጴጥ. ፭፥፱። ፲፮፤ ማቴ. ፳፮፥፳፮—፳፰። ፲፯፤ ሮሜ ፲፪፥፭።

እንጀራ ፡ እንካፈላለንና ። ፲፰ በሥጋ ፡ የሆነውን ፡ እስራኤል ፡ ተመልከቱ ፤ መሥዋዕቱን ፡ የሚ በሉ ፡ የመሠዊያው ፡ ማኅበረተኞች ፡ አይደሉ ምን ? ፲፱ እንግዲህ ፡ ምን ፡ እላለሁ ? ለጣዖት ፡ የተሠዋ ፡ ምናምን ፡ ነው ፡ እላለሁን ? ወይስ ፡ ፳ ጣዖት ፡ ምናምን ፡ እንዲሆን ፡ እላለሁን ? አይ ደለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አሕዛብ ፡ የሚሠዉት ፡ ለአ ጋንንት ፡ እንዲሆን ፡ እንጂ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እንዳይሠዉ ፡ እላለሁ ፤ ከአጋንንትም ፡ ጋር ፡ ፳፩ ማኅበረተኞች ፡ እንድትሆኑ ፡ አልወድም ። የጌ ታን ፡ ጽዋና ፡ የአጋንንትን ፡ ጽዋ ፡ ልትጠጡ ፡ አትችሉም ፤ ከጌታ ፡ ማዕድና ፡ ከአጋንንት ፡ ፳፪ ማዕድ ፡ ልትካፈሉ ፡ አትችሉም ። ወይስ ፡ ጌታን ፡ እናስቀናውን ? እኛስ ፡ ከእርሱ ፡ ይልቅ ፡ እንበ ረታለንን ?

፳፫ ሁሉ ፡ ተፈቅዶልኛል ፥ ሁሉ ፡ ግን ፡ የሚጠ ቅም ፡ አይደለም ፤ ሁሉ ፡ ተፈቅዶልኛል ፥ ነገር ፡ ፳፬ ግን ፡ ሁሉ ፡ የሚያንጽ ፡ አይደለም ። እያንዳ ንዱ ፡ የባልንጀራውን ፡ ጥቅም ፡ እንጂ ፡ አንድ ፡ ፳፭ ስንኳ ፡ የራሱን ፡ ጥቅም ፡ አይፈልግ ። በሥጋ ፡ ገበያ ፡ የሚሸጠውን ፡ ሁሉ ፡ ከሕሊና ፡ የተነሣ ፡ ፳፮ ሳትመራመሩ ፡ ብሉ ፤ ምድርና ፡ በእርስዋ ፡ የሞ ፳፯ ላበት ፡ ሁሉ ፡ የጌታ ፡ ነውና ። ከማያምኑ ፡ ሰዎች ፡ አንዱም ፡ ቢጠራችሁ ፡ ልትሄዱም ፡ ብትወዱ ፡ ከሕሊና ፡ የተነሣ ፡ ሳትመራመሩ ፡ የሚያቀርቡላ ፳፰ ችሁን ፡ ሁሉ ፡ ብሉ ። ማንም ፡ ግን — ይህ ፡ ለጣዖት ፡ የተሠዋ ፡ ነው ፡ ቢላችሁ ፡ ከዚያ ፡ ካስ ታወቃችሁና ፡ ከሕሊና ፡ የተነሣ ፡ አትብሉ ፤ ፳፱ ስለ ፡ ባልንጀራህ ፡ ሕሊና ፡ እንጂ ፡ ስለ ፡ ገዛ ፡ ሕሊናህ ፡ አልናገርም ። አርነቴ ፡ በሌላ ፡ ሰው ፡ ሕሊና ፡ የሚፈረድ ፡ ኧረ ፡ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ፴ እኔም ፡ በጸጋ ፡ ብበላ ፥ በነገሩ ፡ ስለማመሰግን በት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እሰደባለሁ ?

፴፩ እንግዲህ ፡ የምትበሉ ፡ ወይም ፡ የምትጠጡ ፡ ብትሆኑ ፡ ወይም ፡ ማናቸውን ፡ ነገር ፡ ብታደርጉ ፡ ሁሉን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ አድርጉት ። ፴፪፡፴፫ እኔ ፡ ደግሞ ፡ ብዙዎቹ ፡ ይድኑ ፡ ዘንድ ፡ ለጥቅ ማቸው ፡ እንጂ ፡ የራሴን ፡ ጥቅም ፡ ሳልፈልግ ፡ በሁሉ ፡ ነገር ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ እንደማሰኝ ፥ ለአይሁድም ፡ ለግሪክም ፡ ሰዎች ፡ ለእግዚአብ ሔር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ ማሰናከያ ፡ አትሁኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ እኔ ፡ ክርስቶስን ፡ እንደምመስል ፡ እኔን ፡ ምሰሉ ። ፪ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ በሁሉ ፡ ስለምታስቡ ኝና ፡ አሳልፌ ፡ እንደ ፡ ሰጠኋችሁ ፡ ወግን ፡ ፈጽ ማችሁ ፡ ስለ ፡ ያዛችሁ ፡ አመሰግናችኋለሁ ። ፫ ነገር ፡ ግን ፡ የወንድ ፡ ሁሉ ፡ ራስ ፡ ክርስቶስ ፥ የሴትም ፡ ራስ ፡ ወንድ ፥ የክርስቶስም ፡ ራስ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ልታውቁ ፡ እወዳለሁ ። ፬ ራሱን ፡ ተከናንቦ ፡ የሚጸልይ ፡ ወይም ፡ ትንቢት ፡ የሚናገር ፡ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ ራሱን ፡ ያዋርዳል ። ፭ ራስዋን ፡ ሳትሸፍን ፡ ግን ፡ የምትጸልይ ፡ ወይም ፡ ትንቢት ፡ የምትናገር ፡ ሴት ፡ ሁሉ ፡ ራስዋን ፡ ታዋርዳለች ፤ እንደ ፡ ተላጨች ፡ ያህል ፡ አንድ ፡ ነውና ። ፮ ሴትም ፡ ራስዋን ፡ ባትሸፍን ፡ ጠጕር ዋን ፡ ደግሞ ፡ ትቈረጥ ፤ ለሴት ፡ ግን ፡ ጠጕር ዋን ፡ መቈረጥ ፡ ወይም ፡ መላጨት ፡ የሚያሳ ፍር ፡ ከሆነ ፡ ራስዋን ፡ ትሸፍን ። ፯ ወንድ ፡ የእግ ዚአብሔር ፡ ምሳሌና ፡ ክብር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ራሱን ፡ መከናነብ ፡ አይገባውም ፤ ሴት ፡ ግን ፡ የወንድ ፡ ክብር ፡ ናት ። ፰ ሴት ፡ ከወንድ ፡ ናት ፡ እንጂ ፡ ወንድ ፡ ከሴት ፡ አይደለምና ። ፱ ሴት ፡ ስለ ፡ ወንድ ፡ ተፈጠረች ፡ እንጂ ፡ ወንድ ፡ ስለ ፡ ሴት ፡ አልተ ፈጠረምና ። ፲ ስለዚህ ፡ ሴት ፡ ከመላእክት ፡ የተ ነሣ ፡ በራስዋ ፡ ሥልጣን ፡ ሊኖራት ፡ ይገባል ። ፲፩ ነገር ፡ ግን ፡ በጌታ ፡ ዘንድ ፡ ሴት ፡ ያለ ፡ ወንድ ፡ ፲፪ ወንድም ፡ ያለ ፡ ሴት ፡ አይሆንም ። ሴት ፡ ከወ ንድ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ እንዲሁ ፡ ወንድ ፡ ደግሞ ፡ በሴት ፡ ነውና ፤ ሁሉም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ነው ። ፲፫ በእናንተ ፡ በራሳችሁ ፡ መካከል ፡ ፍረዱ ፤ ሴት ፡ ራስዋን ፡ ሳትሸፍን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልት ጸልይ ፡ ይገባታልን ? ፲፬፡፲፭ ወንድ ፡ ጠጕሩን ፡ ቢያ ስረዝም ፡ ነውር ፡ እንዲሆንበት ፥ ሴት ፡ ግን ፡ ጠጕርዋን ፡ ብታስረዝም ፡ ክብር ፡ እንዲሆንላት ፡ ተፈጥሮ ፡ እንኳ ፡ አያስተምራችሁምን ? ጠጕ ርዋ ፡ መጐናጸፊያ ፡ ሊሆን ፡ ተሰጥቶአታልና ። ፲፮ ዳሩ ፡ ግን ፡ ማንም ፡ ሊከራከር ፡ ቢፈቅድ ፥ እኛ ፡ ወይም ፡ የእግዚአብሔር ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያ ናት ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ልማድ ፡ የለንም ።

፲፯ ነገር ፡ ግን ፡ በምትሰበሰቡበት ፡ ጊዜ ፡ ስሚ ከፋ ፡ እንጂ ፡ ለሚሻል ፡ ስላልሆነ ፡ ይህን ፡ ትእዛዝ ፡ ሰስጥ ፡ የማመሰግናችሁ ፡ አይደለም ። ፲፰ በመጀ መሪያ ፡ ወደ ፡ ማኅበር ፡ ስትሰበሰቡ ፡ በመካከላ ችሁ ፡ መለያየት ፡ እንዳለ ፡ እሰማለሁና ፥ በአ ንድ ፡ በኩልም ፡ አምናለሁ ። ፲፱ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ የተፈተኑት ፡ እንዲገለጡ ፡ በመካከላችሁ ፡ ወገ ኖች ፡ ደግሞ ፡ ሊሆኑ ፡ ግድ ፡ ነውና ። ፳ እንግ ዲህ ፡ አብራችሁ ፡ ስትሰበሰቡ ፡ የምትበሉት ፡ የጌታ ፡ እራት ፡ አይደለም ፤ ፳፩ በመብላት ፡ ጊዜ ፡ እያንዳንዱ ፡ የራሱን ፡ እራት ፡ ይበላልና ፥ አን ዱም ፡ ይራባል ፡ አንዱ ፡ ግን ፡ ይሰክራል ። ፳፪ የም ትበሉበቸውና ፡ የምትጠጡበቸው ፡ ቤቶች ፡ የላችሁምን ? ወይስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ማኅ በር ፡ ትንቃላችሁን ፡ እንዳችም ፡ የሌላቸውን ፡ ታሳፍራላችሁን ? ምን ፡ ልበላችሁ ? በዚህ ፡ ነገር ፡ ላመሰግናችሁን ? አላመሰግናችሁም ።

፲ ። [illegible]

፲፩ ። [illegible]

፳፫ ለእናንተ፡ደግሞ፡አሳልፌ፡የሰጠሁትን፡እኔ፡ከጌታ፡ተቀብያለሁና ፤ ጌታ፡ኢየሱስ፡አልፎ፡በተሰጠባት፡በዚያች፡ሌሊት፡እንጀ ፳፬ ራን፡አንሥቶ፡አመሰገነ ÷ ቈርሶም፦ እንካችሁ፡ብሉ ፤ ይህ፡ስለ፡እናንተ፡የሚሆን፡ሥጋዬ፡ነው ፤ ይህን፡ለመታሰቢያዬ፡አድር ፳፭ ጉት፡አለ ። እንደዚሁም፡ከእራት፡በኋላ፡ጽዋውን፡ደግሞ፡አንሥቶ፦ ይህ፡ጽዋ፡በደሜ፡የሚሆን፡አዲስ፡ኪዳን፡ነው ፤ በጠጣችሁት፡ጊዜ፡ሁሉ፡ይህን፡ለመታሰቢያዬ፡አድ ፳፮ ርጉት፡አለ ። ይህን፡እንጀራ፡በበላችሁ፡ጊዜ፡ሁሉ ÷ ይህንም፡ጽዋ፡በጠጣችሁ፡ጊዜ፡ሁሉ፡ጌታ፡እስኪመጣ፡ድረስ፡ሞቱን፡ትናገራላችሁና ።

፳፯ ስለዚህ፡ሳይገባው፡ይህን፡እንጀራ፡የበላ፡ወይም፡የጌታን፡ጽዋ፡የጠጣ፡ሁሉ፡የጌታ፡ ፳፰ ሥጋና፡ደም፡ዕዳ፡አለበት ። ሰው፡ግን፡ራሱን፡ይፈትን ÷ እንዲሁም፡ከእንጀራው፡ ፳፱ ይብላ፡ከጽዋውም፡ይጠጣ ፤ ሳይገባው፡የሚበላና፡የሚጠጣ፡የጌታን፡ሥጋ፡ስለማይለይ፡ ፴ ለራሱ፡ፍርድ፡ይበላልና÷ይጠጣልምና ። ስለዚህ፡በእናንተ፡ዘንድ፡የደከሙና፡የታመሙ፡ብዙዎች፡አሉ፡አያሌዎችም፡አንቀላፍተዋል ። ፴፩ ራሳችንን፡ብንመረምር፡ግን፡ባልተፈረደብ ፴፪ ንም፡ነበር ፤ ነገር፡ግን፡በተፈረደብን፡ጊዜ÷ከዓለም፡ጋር፡እንዳንኰነን፡ስጌታ፡እንገሠጻለን ።

፴፫ ስለዚህ÷ወንድሞቼ፡ሆይ÷ለመብላት፡በተሰበሰባችሁ፡ጊዜ፡እርስ፡በርሳችሁ፡ተጠባበቁ ። ፴፬ ማንም፡የራበው፡ቢኖር፡ለፍርድ፡እንዳትሰበሰቡ፡በቤቱ፡ይብላ ። የቀረውንም፡ነገር፡በመጣሁ፡ጊዜ፡አደነግጋለሁ ።

## ምዕራፍ፡፲፪ ።

፩ ስለ፡መንፈሳዊ፡ነገርም÷ወንድሞች፡ሆይ÷ ፪ ታውቁ፡ዘንድ፡እወዳለሁ ። አሕዛብ፡ሳላችሁ፡በማናቸውም፡ጊዜ፡እንደምትመሩ፡ድምፅ፡ወደሌላቸው፡ወደ፡ጣዖታት፡እንደ፡ተወሰዳ ፫ ችሁ፡ታውቃላችሁ ። ስለዚህ፡ማንም፡በእግዚአብሔር፡መንፈስ፡ሲናገር፦ ኢየሱስ፡የተረገመ፡ነው፡የሚል፡እንደሌለ÷በመንፈስ፡ቅዱስም፡ካልሆነ፡በቀር፦ ኢየሱስ፡ጌታ፡ነው፡ሊል፡አንድ፡እንኳ፡እንዳይችል፡አስታውቃችኋለሁ ።

፬ የጸጋም፡ስጦታ፡ልዩ፡ልዩ፡ነው፡መንፈስ፡ ፭ ግን፡አንድ፡ነው ፤ አገልግሎትም፡ልዩ፡ልዩ፡ ፮ ነው፡ጌታም፡አንድ፡ነው ፤ አሠራርም፡ልዩ፡ልዩ፡ነው÷ሁሉን፡በሁሉ፡የሚያደርግ፡እግ ፯ ዚአብሔር፡ግን፡አንድ፡ነው ። ነገር፡ግን፡መንፈስ፡ቅዱስን፡መግለጥ፡ለእያንዳንዱ፡ለጥቅም፡ይሰጠዋል ። ፰ ለአንዱ፡ጥበብን፡መናገር፡በመንፈስ፡ይሰጠዋልና÷ለአንዱም፡በዚያው፡መንፈስ፡እውቀትን፡መናገር፡ይሰጠዋል ÷ ፱ ለአንዱም፡በዚያው፡መንፈስ፡እምነት ÷ ለአንዱም፡በአንዱ፡መንፈስ፡የመፈወስ፡ስጦታ÷ ፲ ለአንዱም፡ተአምራትን፡ማድረግ÷ለአንዱም፡ትንቢትን፡መናገር÷ለአንዱም፡መናፍስትን፡መለየት÷ለአንዱም፡በልዩ፡ዓይነት፡ልሳን፡መናገር÷ለአንዱም፡በልሳኖች፡የተነገረውን፡መተርጐም፡ይሰጠዋል ፤ ፲፩ ይህን፡ሁሉ፡ግን፡ያ፡አንዱ፡መንፈስ፡እንደሚፈቅድ፡ለእያንዳንዱ፡ለብቻው፡እያከፈለ፡ያደርጋል ።

፲፪ አካልም፡አንድ፡እንደ፡ሆነ፡ብዙም፡ብልቶች፡እንዳሉበት፡ነገር፡ግን፡የአካል፡ብልቶች፡ሁሉ፡ብዙዎች፡ሳሉ፡አንድ፡አካል፡እንደ፡ሆኑ÷ክርስቶስ፡ደግሞ፡እንዲሁ፡ነው ፤ ፲፫ አይሁድ፡ብንሆን፡የግሪክ፡ሰዎችም፡ብንሆን፡ባሪያዎችም፡ብንሆን፡ጨዋዎችም፡ብንሆን፡እኛ፡ሁላችን፡በአንድ፡መንፈስ፡አንድ፡አካል፡እንድንሆን፡ተጠምቀናልና ። ሁላችንም፡አንዱን፡መንፈስ፡ጠጥተናል ።

፲፬ አካል፡ብዙ፡ብልቶች፡እንጂ፡አንድ፡ብልት፡ ፲፭ አይደለምና ። እግር፦ እኔ፡እጅ፡አይደለሁምና፡የአካል፡ክፍል፡አይደለሁም፡ብትል÷ይህን፡በማለትዋ፡የአካል፡ክፍል፡መሆንዋ፡ ፲፮ ይቀራልን ? ጆሮም፦ እኔ፡ዓይን፡አይደለሁምና፡የአካል፡ክፍል፡አይደለሁም፡ቢል÷ይህን፡በማለቱ፡የአካል፡ክፍል፡መሆኑ፡ይቀ ፲፯ ራልን ? አካል፡ሁሉ፡ዓይን፡ቢሆን፡መስማት፡ወዴት፡በተገኘ ? ሁሉም፡መስማት፡ቢሆን፡ ፲፰ ማሽተት፡ወዴት፡በተገኘ ? አሁን፡ግን፡እግዚአብሔር፡እንደ፡ወደደ፡ብልቶችን፡እያን ፲፱ ዳንዳቸው፡ለአካል፡አድርጎአል ። ሁሉም፡አንድ፡ብልት፡ቢሆንስ፡አካል፡ወዴት፡በሆነ ? ፳ ዳሩ፡ግን፡አሁን፡ብልቶች፡ብዙዎች፡ናቸው፡ ፳፩ አካል፡ግን፡አንድ፡ነው ። ዓይን፡እጅን፦ አታስፈልገኝም፡ልትለው፡አትችልም÷ወይም፡ራስ፡ደግሞ፡እግሮችን፦ አታስፈልጉኝም፡ ፳፪ ሊላቸው፡አይችልም ። ነገር፡ግን፡ደካሞች፡የሚመስሉ፡የአካል፡ብልቶች፡ይልቁን፡የሚ ፳፫ ያስፈልጉ፡ናቸው ፤ ከአካልም፡ብልቶች፡ያለ፡ክብሩ፡ሆነው፡የሚመስሉን፡በሚበዛ፡ክብር፡እናለብሳቸዋለን÷በምናፍርባቸውም፡ብልቶ ፳፬ ቻችን፡ክብር፡ይጨመርላቸዋል ፤ ክብር፡ያላ ቸው፡ብልቶቻችን፡ግን፡ይህ፡አያስፈልጋቸውም ። ነገር፡ግን፡ብልቶች፡እርስ፡በርሳቸው፡በትክክል፡ይተሰሰቡ፡ዘንድ፡እንጂ፡በአካል፡መለያየት፡እንዳይሆን÷ለጐደለው፡ብልት፡የሚበልጥ፡ክብር፡እየሰጠ፡እግዚአብሔር፡አካልን፡አገጣጠመው ። ፳፭ አንድም፡

፲፩ ። ፳፫ ገላ. ፩÷፲፪፡፲፱ ። ፳፫—፳፭ ማቴ. ፳፮÷፳፮—፳፰፡ማር. ፲፬÷፳፪—፳፬፡ሉቃ. ፳፪÷፲፱፡፳ ። ፳፯ ዮሐ. ፮÷፶፩—፶፰ ። ፳፰ ፪ ቆሮ. ፲፫÷፭ ።

፲፪ ። ፪ ኤፌ. ፪÷፲፩፡፲፪ ፤ እንግ. ፪÷፲፰ ። ፫ ፩ ዮሐ. ፬÷፪፡፫ ። ፬—፮ ሮሜ ፲፪÷፮፡፯ ፤ ኤፌ. ፬÷፬—፮፡፲፩ ። ፲ ፩ ዮሐ. ፬÷፩ ፤ ሥራ. ፪÷፬ ። ፲፪ ሮሜ ፲፪÷፬፡፭ ። ፲፫ ገላ. ፫÷፳፰ ፤ ዮሐ. ፯÷፴፯—፴፱ ።

ብልት ፡ ቢሠቀይ ፡ ብልቶች ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ይሠቀያሉ ፤ አንድ ፡ ብልትም ፡ ቢከበር ፡ ብልቶች ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።

፳፯ እናንተም ፡ የክርስቶስ ፡ አካል ፡ ናችሁ ፡ እያንዳንዳችሁም ፡ ብልቶች ፡ ናችሁ ። ፳፰ እግዚአብሔርም ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አንዳንዶቹን ፥ አስቀድሞ ፡ሐዋርያትን ፥ ሁለተኛም ፡ ነቢያትን ፥ ሦስተኛም ፡ አስተማሪዎችን ፥ ቀጥሎም ፡ ተአምራት ፡ ማድረግን ፥ ቀጥሎም ፡ የመፈወስን ፡ ስጦታ ፥ እርዳታንም ፥ አገዛዝንም ፥ የልዩ ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ፡ ልሳኖችንም ፡ አድርጎአል ። ፳፱ ሁሉ ፡ ሐዋርያት ፡ ናቸውን ? ሁሉስ ፡ ነቢያት ፡ ናቸውን ? ሁሉስ ፡ አስተማሪዎች ፡ ናቸውን ? ሁሉስ ፡ ተአምራትን ፡ ይሠራሉን ? ፴ ሁሉስ ፡ የመፈወስ ፡ ስጦታ ፡ አላቸውን ? ሁሉስ ፡ በልሳኖች ፡ ይናገራሉን ? ሁሉስ ፡ ይተረጕማሉን ? ፴፩ ነገር ፡ ግን ፡ የሚበልጠውን ፡ የጸጋ ፡ ስጦታ ፡ በብርቱ ፡ ፈልጉ ።

ደግሞም ፡ ከሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ መንገድ ፡ አሳያችኋለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ በሰዎችና ፡ በመላእክት ፡ልሳን ፡ ብናገር ፡ ፍቅር ፡ ግን ፡ ከሌለኝ ፡ እንደሚጮኽ ፡ ናስ ፡ ወይም ፡ እንደሚንሽዋሽዋ ፡ ጸናጽል ፡ ሆኜአለሁ ። ፪ ትንቢትም ፡ ቢኖረኝ ፥ ምሥጢርንም ፡ ሁሉና ፡ እውቀትን ፡ ሁሉ ፡ ባውቅ ፥ ተራሮችንም ፡ እስከ ፈልስ ፡ ድረስ ፡ እምነት ፡ ሁሉ ፡ ቢኖረኝ ፡ ፍቅር ፡ ግን ፡ ከሌለኝ ፡ ከንቱ ፡ ነኝ ። ፫ ድሆችንም ፡ ልመግብ ፡ ያለኝን ፡ ሁሉ ፡ ባካፍል ፥ ሥጋዬንም ፡ ለእሳት ፡ መቃጠል ፡ አሳልፌ ፡ ብሰጥ ፡ ፍቅር ፡ ግን ፡ ከሌለኝ ፡ ምንም ፡ አይጠቅመኝም ።

፬ ፍቅር ፡ ይታገሣል ፥ ቸርነትንም ፡ ያደርጋል ፤ ፍቅር ፡ አይቀናም ፤ ፍቅር ፡ አይመካም ፥ አይታበይም ፤ ፭ የማይገባውን ፡ አያደርግም ፥ የራሱንም ፡ አይፈልግም ፥ አይበሳጭም ፥ በደልን ፡ አይቈጥርም ፤ ፮ ከእውነት ፡ ጋር ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡ እንጂ ፡ ስለ ፡ ዓመፃ ፡ ደስ ፡ አይለውም ፤ ፯ ሁሉን ፡ ይታገሣል ፥ ሁሉን ፡ ያምናል ፥ ሁሉን ፡ ተስፋ ፡ ያደርጋል ፥ በሁሉ ፡ ይጸናል ።

፰ ፍቅር ፡ ለዘወትር ፡ አይወድቅም ፤ ትንቢት ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ ይሻራል ፤ ልሳኖች ፡ ቢሆኑ ፡ ይቀራሉ ፤ እውቀትም ፡ ቢሆን ፡ ይሻራል ። ፱ ከእውቀት ፡ ከፍለን ፡ እናውቃለንና ፥ ከትንቢትም ፡ ከፍለን ፡ እንናገራለንና ፤ ፲ ፍጹም ፡ የሆነ ፡ ሲመጣ ፡ ግን ፡ ተከፍሎ ፡ የነበረው ፡ ይሻራል ። ፲፩ ልጅ ፡ ሳለሁ ፡ እንደ ፡ ልጅ ፡ እናገር ፡ ነበር ፥ እንደ ፡ ልጅም ፡ አስብ ፡ ነበር ፥ እንደ ፡ ልጅም ፡ እቈጥር ፡ ነበር ፤ ጕልማሳ ፡ ሆኜ ፡ ግን ፡ የልጅነትን ፡ ጠባይ ፡ ሽሬአለሁ ። ፲፪ ዛሬስ ፡ በመስተዋት ፡ በድንግዝግዝ ፡ እንደምናይ ፡ ነን ፥ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ እናያለን ፤ ዛሬስ ፡ ከእውቀት ፡ ከፍዬ ፡ አውቃለሁ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ታወቅሁ ፡ አውቃለሁ ። ፲፫ እንዲህም ፡ ከሆነ ፥ እምነት ፡ ተስፋ ፡ ፍቅር ፡ እነዚህ ፡ ሦስቱ ፡ጸንተው ፡ ይኖራሉ ፤ ከእነዚህም ፡ የሚበልጠው ፡ ፍቅር ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩ ፍቅርን ፡ ተከታተሉ ፥ መንፈሳዊ ፡ ስጦታንም ፡ ይልቁንም ፡ ትንቢት ፡ መናገርን ፡ በብርቱ ፡ ፈልጉ ። ፪ በልሳን ፡ የሚናገርስ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እንጂ ፡ ለሰው ፡ አይናገርም ፤ የሚያስተውለው ፡ የለምና ፥ በመንፈስ ፡ ግን ፡ ምሥጢርን ፡ ይናገራል ፤ ፫ ትንቢትን ፡ የሚናገር ፡ ግን ፡ ለማነጽና ፡ ለመምከር ፡ ለማጽናናትም ፡ ለሰው ፡ ይናገራል ። ፬ በልሳን ፡ የሚናገር ፡ ራሱን ፡ ያንጻል ፤ ትንቢትን ፡ የሚናገር ፡ ግን ፡ ማኅበሩን ፡ ያንጻል ። ፭ ሁላችሁ ፡ በልሳኖች ፡ ልትናገሩ ፡ እወድ ፡ ነበር ፥ ትንቢትን ፡ ልትናገሩ ፡ ግን ፡ ከዚህ ፡ ይልቅ ፡ እወዳለሁ ፤ ማኅበሩ ፡ ይታነጽ ፡ ዘንድ ፡ ንግግሩን ፡ባይተረጕም ፡ በልሳኖች ፡ ከሚናገር ፡ ትንቢትን ፡ የሚናገር ፡ ይበልጣል ።

፮ አሁን ፡ ግን ፥ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ እናንተ ፡ መጥቼ ፡ በልሳኖች ፡ ብናገር ፥ በመግለጥ ፡ ወይም ፡ በእውቀት ፡ ወይም ፡ በትንቢት ፡ ወይም ፡ በትምህርት ፡ ካልነገርኋችሁ ፡ ምን ፡ እጠቅማችኋለሁ ? ፯ ነፍስ ፡ የሌለበት ፡ ነገር ፡ እንኳ ፡ዋሽንትም ፡ ክራርም ፡ ቢሆን ፡ ድምፅ ፡ ሲሰጥ ፡ የድምፁን ፡ ልዩነት ፡ ባይገልጥ ፡ በዋሽንት ፡ የሚነፋው ፡ ወይስ ፡ በክራር ፡ የሚመታው ፡ መዝሙር ፡ እንዴት ፡ ይታወቃል ? ፰ ደግሞም ፡ መለከት ፡ የማይገለጥን ፡ ድምፅ ፡ ቢሰጥ ፡ ለጦርነት ፡ ማን ፡ ይዘጋጃል ? ፱ እንዲሁ ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ የተገለጠውን ፡ ቃል ፡ በአንደበት ፡ ባትናገሩ ፡ ሰዎች ፡ የምትናገሩትን ፡ እንዴት ፡ አድርገው ፡ ያስተውሉታል ? ለነፋስ ፡ የምትናገሩ ፡ ትሆናላችሁና ። ፲ በዓለም ፡ምናልባት ፡ ቍጥር ፡ የሌለው ፡ የቋንቋ ፡ ዓይነት ፡ ይኖራል ፡ ቋንቋም ፡ የሌለው ፡ ሕዝብ ፡ የለም ፤ ፲፩ እንግዲህ ፡ የቋንቋውን ፡ ፍች ፡ባላውቅ ፡ ለሚናገረው ፡ እንግዳ ፡ እሆናለሁ ፥ የሚናገረውም ፡ ለእኔ ፡ እንግዳ ፡ ይሆናል ። ፲፪ እንዲሁ ፡ ደግሞ ፡ እናንተ ፡ መንፈሳዊ ፡ ስጦታን ፡ በብርቱ ፡ የምትፈልጉ ፡ ከሆናችሁ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ለማነጽ ፡ እንዲበዛላችሁ ፡ ፈልጉ ።

፲፫ ስለዚህ ፡ በልሳን ፡ የሚናገር ፡ እንዲተረጕም ፡ ይጸልይ ። ፲፬ በልሳን ፡ ብጸልይ ፡ መንፈሴ ፡ ይጸልያል ፡ አእምሮዬ ፡ግን ፡ ያለ ፡ ፍሬ ፡ ነው ። ፲፭ እንግዲህ ፡ ምንድር ፡ ነው ? በመንፈስ ፡ እጸልያለሁ ፡ በአእምሮም ፡ ደግሞ ፡ እጸልያለሁ ፤ በመ

፳፪ ። ፳፰ ፤ ኤፌ. ፬ ፥ ፲፩ ።
፳፫ ። ፪ ፤ ማቴ. ፲፯ ፥ ፳ ። ፬ ፤ ም. ፪ ፥ ፯ ፤ ምሳ. ፲ ፥ ፲፪ ። ፭ ፤ ፊልጵ. ፪ ፥ ፬ ። ፯ ፤ ሮሜ ፲፭ ፥ ፩ ፤ ፪ ጢሞ. ፪ ። ፲፪ ፤ ፪ ቆሮ. ፫ ፥ ፲፰ ። ፲፫ ፤ ፩ ተሰ. ፩ ፥ ፫ ፤ ፩ ጢሞ. ፩ ፥ ፲፬ ።
፳፬ ። ፩ ፤ ም. ፲፫ ፥ ፭ ፤ ፴ ። ፭ ፤ ዘኍል. ፲፩ ፥ ፳፱ ። ፲፩ ፤ ኤፌ. ፭ ፥ ፲፱ ፤ ፲፱ ፤ መዝ. ፵፯ ፥ ፯ ።

ንፈስ ፡ እዘምራለሁ ፡ በአእምሮም ፡ ደግሞ ፡ እዘ
፲፮ ምራለሁ ። እንዲያማ ፡ ካልሆነ ፥ አንተ ፡ በመ
ንፈስ ፡ ብትባርክ ፡ ባልተማሩት ፡ ስፍራ ፡ የተቀ
መጠው ፡ የምትለውን ፡ ካላወቀ ፡ እንዴት ፡ አድ
፲፯ ርጎ ፡ ለምስጋናህ ፡ አሜን ፡ ይላል ? አንተማ ፡
መልካም ፡ ታመሰግናለህ ፥ ሌላው ፡ ግን ፡ አይ
፲፰ ታነጽበትም ። ከሁላችሁ ፡ ይልቅ ፡ በልሳኖች ፡
እናገራለሁና ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግናለሁ ፤
፲፱ ነገር ፡ ግን ፡ ሌሎችን ፡ ደግሞ ፡ እስተምር ፡ ዘንድ ፡
በማኅበር ፡ እልፍ ፡ ቃላት ፡ በልሳን ፡ ከመናገር ፡
ይልቅ ፡ አምስት ፡ ቃላት ፡ በአእምሮዬ ፡ ልናገር ፡
እወዳለሁ ።

፳ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ በአእምሮ ፡ሕፃናት ፡ አት
ሁኑ ፤ ስክፋት ፡ ነገር ፡ ሕፃናት ፡ ሁኑ ፡ እንጂ ፡
፳፩ በአእምሮ ፡ የበሰሉ ፡ ሁኑ ። ሌሎችን ፡ ልሳ
ኖች ፡ በሚናገሩ ፡ ሰዎችና ፡ በሌላ ፡ እንደበት ፡
ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ እናገራቸዋለሁ ፥ እንዲሀም ፡
ቢሆን ፡ አይሰሙኝም ፡ ይላል ፡ ጌታ ፡ ተብሎ ፡
፳፪ በሕግ ፡ ተጽፎአል ። እንግዲያስ ፡ በልሳኖች ፡
መናገር ፡ ስማያምኑ ፡ ምልክት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
ለሚያምኑ ፡ አይደለም ፥ ትንቢት ፡ ግን ፡ ለሚ
፳፫ ያምኑ ፡ እንጂ ፡ ለማያምኑ ፡ አይደለም ። እንግ
ዲህ ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ አብረው ፡ ቢሰበሰቡ ፡
ሁሉም ፡ በልሳኖች ፡ ቢናገሩና ፡ ያልተማሩ ፡
ወይም ፡ የማያምኑ ፡ ሰዎች ፡ ቢገቡ ፡ —አብደ
፳፬ ዋል ፡ አይሉምን ? ሁሉ ፡ ትንቢት ፡ ቢና
ገሩ ፡ ግን ፡ የማያምን ፡ ወይም ፡ ያልተማረ ፡ ሰው ፡
ቢገባ ፡ በሁሉ ፡ ይወቀሳል ፥ በሁሉም ፡ ይመረ
፳፭ መራል ፤ በልቡም ፡ የተሰወረ ፡ ይገለጣል ፡ እን
ዲሁም ፡ —እግዚአብሔር ፡ በእውነት ፡ በመካከ
ላቸው ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ እየተናገረ ፡ በፊቱ ፡ ወድቆ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ይሰግዳል ።

፳፮ እንግዲህ ፥ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ምንድር ፡
ነው ? በምትሰበሰቡበት ፡ ጊዜ ፡ ለእያንዳንዱ ፡
መዝሙር ፡ አለው ፥ ትምህርት ፡ አለው ፤ መግ
ለጥ ፡ አለው ፥ በልሳን ፡ መናገር ፡ አለው ፤ መተ
፳፯ ርጎም ፡ አለው ፤ ሁሉ ፡ ስማነጽ ፡ ይሁን ። በል
ሳን ፡ የሚናገር ፡ ቢኖር ፡ ሁለት ፡ ወይም ፡ ቢበዛ ፡
ሦስት ፡ ሆነው ፡ በተራቸው ፡ ይናገሩ ፡ አንዱም ፡
፳፰ ይተርጉም ፤ የሚተረጉም ፡ባይኖር ፡ ግን ፡ በማ
ኅበር ፡ መካከል ፡ ዝም ፡ ይበልና ፡ ለራሱና ፡ ለእ
፳፱ ግዚአብሔር ፡ ይናገር ። ነቢያትም ፡ ሁለት ፡
ወይም ፡ ሦስት ፡ ሆነው ፡ ይናገሩ ፡ ሌሎችም ፡
፴ ይለዩአቸው ፤ በዚያ ፡ ለሚቀመጥ ፡ ለሌላ ፡ ግን ፡
አንድ ፡ ነገር ፡ ቢገለጥለት ፡ ፊተኛው ፡ ዝም ፡
፴፩ ይበል ። ሁሉም ፡ እንዲማሩ ፡ ሁሉም ፡ እንዲ
መከሩ ፡ ሁላችሁ ፡ በእያንዳንዳችሁ ፡ ትንቢት ፡
፴፪ ልትናገሩ ፡ ትችላላችሁ ። የነቢያትም ፡ መንፈ
ስት ፡ ለነቢያት ፡ ይገዛሉ ፤ እግዚአብሔርስ ፡ የሰ ፴፫
ላም ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የሁከት ፡ አምላክ ፡
አይደለምና ፤ በቅዱሳንም ፡ አብያተ ፡ ክርስቲ
ያናት ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ነው ።

፴፬ ሴቶች ፡ በማኅበር ፡ ዝም ፡ ይበሉ ፤ ሕግ ፡ ደግሞ ፡
እንደሚል ፡ እንዲገዙ ፡ እንጂ ፡ እንዲናገሩ ፡ አል
፴፭ ተፈቀደላቸውምና ። ለሴት ፡ በማኅበር ፡ መካ
ከል ፡ መናገር ፡ነውር ፡ ነውና ፥ ምንም ፡ ሊማሩ ፡
ቢወዱ ፡ በቤታቸው ፡ በሎቻቸውን ፡ ይጠይቁ ።
፴፮ ምን ፡ ነው ? የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ የወጣ ፡
ከእናንተ ፡ነውን ? ወይስ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ብቻ ፡
ደርሶአልን ?

፴፯ ማንም ፡ ነቢይ ፡ ወይም ፡ መንፈሳዊ ፡ የሆነ ፡
ቢመስለው ፡ ይህች ፡ የጻፍሁላችሁ ፡ የጌታ ፡ ትእ
፴፰ ዛዝ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ ይወቅ ፤ ማንም ፡ የማያ
፴፱ ውቅ ፡ ቢኖር ፡ ግን ፡ አይወቅ ። ስለዚህ ፥ ወን
ድሞች ፡ ሆይ ፥ ትንቢት ፡ ለመናገር ፡ በብርቱ ፡
ፈልጉ ፥ በልሳኖች ፡ ከመናገርም ፡ አትከልክሉ ፤
፵ ነገር ፡ ግን ፡ ሁሉ ፡ በአገባብና ፡ በሥርዓት ፡ ይሁን ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ የሰበክሁላችሁን ፡ ደግ
ሞም ፡ የተቀበላችሁትን ፡ በእርሱም ፡ ደግሞ ፡
የቆማችሁበትን ፡ በእርሱም ፡ ደግሞ ፡ የምትድ
፪ ኑበትን ፡ ወንጌል ፡ አሳስባችኋለሁ ፤ በከንቱ ፡
ካላመናችሁ ፡ በቀር ፥ ብታስቡት ፥ በምን ፡ ቃል ፡
እንደ ፡ ሰበክሁላችሁ ፡ አሳስባችኋለሁ ።

፫ እኔ ፡ ደግሞ ፡ የተቀበልሁትን ፡ ከሁሉ ፡ በፊት ፡
አሳልፌ ፡ ሰጠኋችሁ ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ — መጽ
ሐፍ ፡ እንደሚል ፡ ክርስቶስ ፡ ስለ ፡ ኃጢአታ
፬ ችን ፡ ሞተ ፥ ተቀበረም ፥ መጽሐፍም ፡ እንደ
፭ ሚል ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ተነሣ ፥ ለኬ
፮ ፋም ፡ ታየ ፡ በኋላም ፡ ለአሥራ ፡ ሁለቱ ፤ ከዚ
ያም ፡ በኋላ ፡ ከአምስት ፡ መቶ ፡ ለሚበዙ ፡ ወን
ድሞች ፡ በአንድ ፡ ጊዜ ፡ ታየ ፤ ከእነርሱም ፡
የሚበዙቱ ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ አሉ ፡ አንዳንዶች ፡
፯ ግን ፡ አንቀላፍተዋል ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ለያዕ
፰ ቆብ ፡ ኋላም ፡ ለሐዋርያት ፡ ሁሉ ፡ ታየ ፤ ከሁ
ሉም ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ጭንጋፍ ፡ ለምሆን ፡ ለእኔ ፡
፱ ደግሞ ፡ ታየኝ ። እኔ ፡ ከሐዋርያት ፡ ሁሉ ፡ የማ
ንስ ፡ ነኝና ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲ
ያን ፡ ስላሳደድሁ ፡ ሐዋርያ ፡ ተብዬ ፡ ልጠራ ፡
፲ የማይገባኝ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡
የሆንሁ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ ለእኔም ፡ የተሰጠኝ ፡ ጸጋው ፡
ከንቱ ፡ አልነበረም ፡ ከሁላቸው ፡ ይልቅ ፡ ግን ፡
ደከምሁ ፥ ዳሩ ፡ ግን ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ያለው ፡ የእ
ግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እኔ ፡ አይደለ
፲፩ ሁም ። እንግዲህስ ፡ እኔ ፡ ብሆን ፡ እነርሱም ፡

፲፬ ። ፲፮ ፤ ፩ ዜና ፲፮ ፥ ፴፮ ፤ መዝ· ፻፮ ፥ ፵፰ ። ፳ ፤ ኤፌ· ፬ ፥ ፲፬ ፤ ሮሜ ፲፮ ፥ ፲፱ ። ፳፩ ፤ ኢሳ· ፳፰ ፥ ፲፩ ፡ ፲፪ ። ፴፫ ፤ [illegible] ፥ ፲፮ ። ፴፬ ፤ ኢሳ· ፵፩ ፥ ፲፱ ፤ ዘፍ· ፫ ፥ ፲፮ ። ፴፮ ፤ ፩ ተሰ· ፩ ፥ ፲፱—፳፩ ። ፵ ፤ ፩ ጴጥ· ፬ ፥ ፲፩ ፡ ፲፪ ፤ [illegible] ፳ ፥ ፲፬ ። ፴፯ ፤ ፩ ዮሐ· ፬ ፥ ፮ ። ፵ ፤ ቆላ· ፪ ።

፲፭ ። ፫ ፤ ሮሜ· ፲፭ ፥ ፳፫ ፤ ኢሳ· ፶፫ ፥ ፩—፲፪ ፤ የሐዋ· ፫ ፥ ፲፰ ። ፬ ፤ መዝ· ፲፮ ፥ ፲ ፤ የሐዋ· ፪ ፥ ፳፭—፴፩ ፤ ማቴ· ፲፪ ፥ ፵ ። ፭ ፤ ሉቃ· ፳፬ ፥ ፴፬ ፡ ፴፮ ። ፮ ፤ የሐዋ· ፩ ፥ ፫ ፡ ፬ ። ፰ ፤ ዮሐ· ፬ ፥ ፭ ። ፱ ፤ ኤፌ· ፫ ፥ ፰ ፤ የሐዋ· ፰ ፥ ፫ ። ፲ ፤ ፪ ቆሮ· ፫ ፥ ፭ ፤ ፲፩ ፥ ፳፫ ።

ቢሆኑ ፡ እንዲሁ ፡ እንሰብካለን ፡ እንዲሁም ፡ አመ
ናችሁ ።

፲፪ ክርስቶስ ፡ ከሙታን ፡ እንደ ፡ ተነሣ ፡ የሚሰ
በክ ፡ ከሆነ ፡ ግን ፡ ከእናንተ ፡ አንዳንዶቹ ፡— ትን
፲፫ ሣኤ ፡ ሙታን ፡ የለም ፡ እንዴት ፡ ይላሉ ? ትን
ሣኤ ፡ ሙታንስ ፡ ከሌለ ፡ ክርስቶስ ፡ አልተነሣማ ፤
፲፬ ክርስቶስም ፡ ካልተነሣ ፡ እንግዲያስ ፡ ስብከታ
ችን ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ እምነታችሁም ፡ ደግሞ ፡
፲፭ ከንቱ ፡ ናት ፤ ደግሞም ፡— ክርስቶስን ፡ አስነሣ
ቶታል ፡ ብለን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ስለ ፡
መሰከርን ፥ ሐሰተኞች ፡ የእግዚአብሔር ፡ ምስክ
ሮች ፡ ሆነን ፡ ተገኝተናል ፤ ሙታን ፡ ግን ፡ የማይ
፲፮ ነሡ ፡ ከሆነ ፡ እርሱን ፡ አላስነሣውም ። ሙታን ፡
፲፯ የማይነሡ ፡ ከሆነ ፡ ክርስቶስ ፡ አልተነሣማ ፤ ክር
ስቶስም ፡ ካልተነሣ ፡ እምነታችሁ ፡ ከንቱ ፡ ናት ፤
አስከ ፡ አሁን ፡ ድረስ ፡ በኃጢአታችሁ ፡ አላችሁ ።
፲፰ እንግዲያስ ፡ በክርስቶስ ፡ ያንቀላፉት ፡ ደግሞ ፡
፲፱ ጠፍተዋል ። በዚች ፡ ሕይወት ፡ ብቻ ፡ ክርስቶ
ስን ፡ ተስፋ ፡ ያደረግን ፡ ከሆነ ፥ ከሰው ፡ ሁሉ ፡
ይልቅ ፡ ምስኪኖች ፡ ነን ።

፳ አሁን ፡ ግን ፡ ክርስቶስ ፡ ላንቀላፉት ፡ በኵ
፳፩ ራት ፡ ሆኖ ፡ ከሙታን ፡ ተነሥቶአል ። ሞት ፡
በሰው ፡ በኩል ፡ ስለ ፡ መጣ ፡ ትንሣኤ ፡ ሙታን ፡
፳፪ በሰው ፡ በኩል ፡ ሆኖአልና ። ሁሉ ፡ በአዳም ፡
እንደሚሞቱ ፡ እንዲሁ ፡ ሁሉ ፡ በክርስቶስ ፡
፳፫ ደግሞ ፡ ሕያዋን ፡ ይሆናሉና ። ነገር ፡ ግን ፡ እያ
ንዳንዱ ፡ በራሱ ፡ ተራ ፡ ይሆናል ፤ ክርስቶስ ፡
እንደ ፡ በኵራት ፡ ነው ፥ በኋላም ፡ በመምጣቱ ፡
፳፬ ለክርስቶስ ፡ የሆኑት ፡ ናቸው ፤ በኋላም ፥ መንግ
ሥቱን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለአባቱ ፡ አሳልፎ ፡
በሰጠ ፡ ጊዜ ፡ አለቅነትንም ፡ ሁሉና ፡ ሥልጣንን ፡
ሁሉ ፡ ኃይልንም ፡ በሻረ ፡ ጊዜ ፥ ፍጻሜ ፡ ይሆ
፳፭ ናል ። ጠላቶቹን ፡ ሁሉ ፡ ከእግሩ ፡ በታች ፡ እስ
፳፮ ኪያደርግ ፡ ድረስ ፡ ሊነግሥ ፡ ይገባዋልና ። የኋ
፳፯ ለኛው ፡ ጠላት ፡ የሚሻረው ፡ ሞት ፡ ነው ፤ ሁሉን ፡
ከእግሩ ፡ በታች ፡ አስገዝቶአልና ። ነገር ፡ ግን ፡—
ሁሉ ፡ ተገዝቶአል ፡ ሲል ፥ ሁሉን ፡ ካስገዛለት ፡
፳፰ በቀር ፡ መሆኑ ፡ ግልጥ ፡ ነው ። ሁሉ ፡ ከተገዛ
ለት ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሁሉ ፡ በሁሉ ፡
ይሆን ፡ ዘንድ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ልጁ ፡ ራሱ ፡ ደግሞ ፡
ሁሉን ፡ ላስገዛለት ፡ ይገዛል ።

፳፱ እንዲያማ ፡ ካልሆነ ፥ ስለ ፡ ሙታን ፡ የሚጠ
መቁ ፡ ምን ፡ ያደርጋሉ ? ሙታንስ ፡ ከቶ ፡ የማ
ይነሡ ፡ ከሆነ ፥ ስለ ፡ እነርሱ ፡ የሚጠመቁ ፡ ስለ ፡
፴ ምንድር ፡ ነው ? እኛስ ፡ ዘወትር ፡ በሚያስፈራ ፡
፴፩ ኑሮ ፡ የምንኖር ፡ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ? በጌታ
ችን ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ባለኝ ፡ በእናንተ ፡
ትምክህት ፡ እየማልሁ ፥ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥
፴፪ ዕለት ፡ ዕለት ፡ እሞታለሁ ። እንደ ፡ ሰው ፡ በኤ
ፌሶን ፡ ከአውሬ ፡ ጋር ፡ ከታገልሁ ፥ ሙታንስ ፡
የማይነሡ ፡ ከሆነ ፥ ምን ፡ ይጠቅመኛል ? ነገ ፡
፴፫ እንሞታለንና ፡ እንብላና ፡ እንጠጣ ። አትሳቱ ፤
ክፉ ፡ ባልንጀርነት ፡ መልካሙን ፡ አመል ፡ ያጠ
፴፬ ፋል ። በጽድቅ ፡ ንቁ ፡ ኃጢአትንም ፡ አትሥሩ ፤
እግዚአብሔርን ፡ የማያውቁ ፡ አሉና ፤ አሳፍራ
ችሁ ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡ እላለሁ ።

፴፭ ነገር ፡ ግን ፡ ሰው ፡— ሙታን ፡ እንዴት ፡ ይነሣሉ ?
በምንስ ፡ ዓይነት ፡ አካል ፡ ይመጣሉ ? የሚል ፡
፴፮ ይኖር ፡ ይሆናል ። አንተ ፡ ሞኝ ፥ አንተ ፡ የምት
፴፯ ዘራው ፡ ካልሞተ ፡ ሕያው ፡ አይሆንም ፤ የምት
ዘራውም ፤ ስንዴ ፡ ቢሆን ፡ ከሌላም ፡ ዓይነት ፡
የአንዱ ፡ ቢሆን ፥ ቅንጣት ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
የምትዘራው ፡ የሚሆነውን ፡ አካል ፡ አይደለም ፤
፴፰ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ አካልን ፡
ይሰጠዋል ፡ ከዘሮችም ፡ ለእያንዳንዱ ፡ የገዛ ፡ አካ
፴፱ ሉን ፡ ይሰጠዋል ። ሥጋ ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ አይደ
ለም ፥ የሰው ፡ ሥጋ ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ነው ፥ የእን
ስሳም ፡ ሥጋ ፡ ሌላ ፡ ነው ፥ የወፎችም ፡ ሥጋ ፡
፵ ሌላ ፡ ነው ፥ የዓሣም ፡ ሥጋ ፡ ሌላ ፡ ነው ። ደግሞ ፡
ሰማያዊ ፡ አካል ፡ አለ ፥ ምድራዊም ፡ አካል ፡
አለ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የሰማያዊ ፡ አካል ፡ ክብር ፡
ልዩ ፡ ነው ፥ የምድራዊም ፡ አካል ፡ ክብር ፡ ልዩ ፡
፵፩ ነው ። የፀሐይ ፡ ክብር ፡ አንድ ፡ ነው ፡ የጨረ
ቃም ፡ ክብር ፡ ሌላ ፡ ነው ፡ የከዋክብትም ፡ ክብር ፡
ሌላ ፡ ነው ፤ ለክብር ፡ አንዱ ፡ ኮከብ ፡ ከሌላው ፡
ኮከብ ፡ ይለያልና ።

፵፪ የሙታን ፡ ትንሣኤ ፡ ደግሞ ፡ እንዲሁ ፡ ነው ።
በመበስበስ ፡ ይዘራል ፥ ባለመበስበስ ፡ ይነሣል ፤
፵፫ በውርደት ፡ ይዘራል ፥ በክብር ፡ ይነሣል ፤ በድ
፵፬ ካም ፡ ይዘራል ፥ በኃይል ፡ ይነሣል ፤ ፍጥረታዊ ፡
አካል ፡ ይዘራል ፥ መንፈሳዊ ፡ አካል ፡ ይነሣል ።
ፍጥረታዊ ፡ አካል ፡ ካለ ፡ መንፈሳዊ ፡ አካል ፡
፵፭ ደግሞ ፡ አለ ። እንዲሁ ፡ ደግሞ ፡— ፊተኛው ፡
ሰው ፡ አዳም ፡ ሕያው ፡ ነፍስ ፡ ሆነ ፡ ተብሎ ፡ ተጽ
ፎአል ፤ ኋለኛው ፡ አዳም ፡ ሕይወትን ፡ የሚሰጥ ፡
፵፮ መንፈስ ፡ ሆነ ። ነገር ፡ ግን ፡ አስተድሞ ፡ ፍጥረ
ታዊው ፡ ቀጥሎም ፡ መንፈሳዊው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
፵፯ መንፈሳዊው ፡ መጀመሪያው ፡ አይደለም ። የፊ
ተኛው ፡ ሰው ፡ ከመሬት ፡ መሬታዊ ፡ ነው ፤ ሁለ
፵፰ ተኛው ፡ ሰው ፡ ከሰማይ ፡ ነው ። መሬታዊው ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ መሬታውያን ፡ የሆኑት ፡ ደግሞ ፡
እንዲሁ ፡ ናቸው ፥ ሰማያዊው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ሰማያውያን ፡ የሆኑት ፡ ደግሞ ፡ እንዲሁ ፡ ናቸው ።
፵፱ የዚያንም ፡ የመሬታዊውን ፡ መልክ ፡ እንደ ፡ ለበ
ስን ፡ የሰማያዊውን ፡ መልክ ፡ ደግሞ ፡ እንለብሳ
፶ ለን ። ነገር ፡ ግን ፥ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡
እላለሁ ፡— ሥጋና ፡ ደም ፡ የእግዚአብሔርን ፡
መንግሥት ፡ ሊወርሱ ፡ አይችሉም ፥ የሚበሰብ

፲፭ ። ፲፪ ፤ ፪ ጢሞ ፪ ፥ ፲፰ ። ፲፭ ፤ የሐዋ ፪ ፥ ፴፪ ። ፲፯ ፤ ሮሜ ፬ ፥ ፳፭ ። ፳ ፤ ቆላ ፩ ፥ ፲፰ ። ፳፩ ፤ ሮሜ ፭ ፥ ፲፪ ፤ ፲፯ ፥
፳፰ ። ፳፫ ፤ ፩ ተሰ ፬ ፥ ፲፮ ፣ ፲፯ ። ፳፬ ፤ ኤፌ ፩ ፥ ፳፩ ፣ ፳፪ ፤ ራእ ፲፩ ፥ ፲፭ ። ፳፭ ፤ መዝ ፻፲ ፥ ፩ ። ፳፯ ፤ ፊል ፫ ፥ ፳፩ ፤
ዕብ ፪ ፥ ፰ ። ፳፰ ፤ መዝ ፰ ፥ ፮ ፤ ማቴ ፲፩ ፥ ፳፯ ። ፴ ፤ ፪ ቆሮ ፲፩ ፥ ፳፮ ። ፴፩ ፤ ፩ ተሰ ፪ ፥ ፲፱ ፤ ሮሜ ፰ ፥ ፴፮ ። ፴፪ ፤
ኢሳ ፳፪ ፥ ፲፫ ። ፴፬ ፤ ሮሜ ፲፫ ፥ ፲፩ ፣ ፲፪ ። ፴፮ ፤ ዮሐ ፲፪ ፥ ፳፬ ። ፵፪ ፤ ዘፍጥ ፩ ፥ ፲፩ ። ፵፫ ፤ ፊልጵ ፫ ፥ ፳፩ ።
፵፭ ፤ ዘፍጥ ፪ ፥ ፯ ፤ ዮሐ ፭ ፥ ፳፩ ፤ ሮሜ ፭ ፥ ፲፬ ። ፵፯ ፤ ዘፍጥ ፫ ፥ ፲፱ ፤ ዮሐ ፫ ፥ ፴፩ ። ፶ ፤ ዮሐ ፫ ፥ ፭ ፣ ፮ ።

ሰውም፡የማይበሰብሰውን፡አይወርስም ።

፶፩፡፶፪፤ እነሆ÷አንድ፡ምሥጢር፡እነግራችኋለሁ ፤ ሁላችን፡አናንቀላፋም፡ነገር፡ግን፡የኋለኛው፡መለከት፡ሲነፋ፡ሁላችን፡በድንገት፡በቅጽበት፡ዓይን፡እንለወጣለን ፤ መለከት፡ይነፋልና፡ሙታንም፡የማይበሰብሱ፡ሆነው፡ይነሣሉ፡እኛም፡እንለወጣለን ።

፶፫፤ ይህ፡የሚበሰብሰው፡የማይበሰብሰውን፡ሊለብስ፡ይህም፡የሚሞተው፡የማይሞተውን፡ሊለብስ፡ይገባዋልና ።

፶፬፤ ዳሩ፡ግን፡ይህ፡የሚበሰብሰው፡የማይበሰብሰውን፡ሲለብስ፡ይህም፡የሚሞተው፡የማይሞተውን፡ሲለብስ÷በዚያን፡ጊዜ—ሞት፡ድል፡በመነሣት፡ተዋጠ፡ተብሎ፡የተጻፈው፡ቃል፡ይፈጸማል ።

፶፭፤ ሞት፡ሆይ÷መውጊያህ፡የት፡አለ ? ሲኦል፡ሆይ÷ድል፡መንሣትህ፡የት፡አለ ?

፶፮፤ የሞት፡መውጊያ፡ኃጢአት፡ነው፡የኃጢአትም፡ኃይል፡ሕግ፡ነው ፤

፶፯፤ ነገር፡ግን፡በጌታችን፡በኢየሱስ፡ክርስቶስ፡በኩል፡ድል፡መንሣትን፡ለሚሰጠን፡ለእግዚአብሔር፡ምስጋና፡ይሁን ።

፶፰፤ ስለዚህ÷የተወደዳችሁ፡ወንድሞቼ፡ሆይ÷ድካማችሁ፡በጌታ፡ከንቱ፡እንዳይሆን፡አውቃችኋልና፡የምትደላደሉ÷የማትነቃነቁም÷የጌታም፡ሥራ፡ሁልጊዜ፡የሚበዛላችሁ፡ሁኑ ።

## ምዕራፍ፡፲፮ ።

፩፤ ለቅዱሳንም፡ገንዘብን፡ስለ፡ማዋጣት÷ለገላትያ፡አብያተ፡ክርስቲያናት፡እንደ፡ደነገግሁት፡እናንተ፡ደግሞ፡እንዲሁ፡አድርጉ ።

፪፤ እኔ፡ስመጣ፡ይህ፡የገንዘብ፡ማዋጣት፡ያን፡ጊዜ፡እንዳይሆን÷ከእናንተ፡እያንዳንዱ፡በየሰምንቱ፡በፊተኛው፡ቀን፡እንደ፡ቀናው፡መጠን፡እያስቀረ፡በቤቱ፡ያስቀምጥ ።

፫፤ ስመጣም፡ማናቸውም፡ቢሆኑ፡የታመኑ፡የሚመስሉአችሁ፡ሰዎች፡ቸርነታችሁን፡ወደ፡ኢየሩሳሌም፡ያደርሱ፡ዘንድ፡ደብዳቤ፡ሰጥቼ፡እልካቸዋለሁ ፤

፬፤ እኔ፡ደግሞ፡ልሄድ፡የሚገባኝ፡ብሆን፡ከእኔ፡ጋር፡አብረው፡ይሄዳሉ ።

፭፤ በመቄዶንያም፡ስልፍ፡ወደ፡እናንተ፡እመጣለሁ ፤ በመቄዶንያ፡አድርጌ፡አልፋለሁና ፤

፮፤ እናንተም፡ወደምሄድበት፡ወደ፡ማናቸውም፡ስፍራ፡በጕዞዬ፡እንድትረዱኝ፡ምናልባት፡በእናንተ፡ዘንድ፡እቆይ፡ወይም፡እከርም፡ይሆናል ።

፯፤ አሁን፡እግረ፡መንገዱን፡ስልፍ፡ልጐበኛችሁ፡አልወድምና ፤ ጌታ፡ቢፈቅደው፡የሆነውን፡ዘመን፡በእናንተ፡ዘንድ፡ልሰነብት፡ተስፋ፡አደርጋለሁና ።

፰፤ በኤፌሶን፡ግን፡እስከ፡በዓለ፡ኀምሳ፡ድረስ፡እሰነብታለሁ ።

፱፤ ሥራ፡የሞላበት፡ትልቅ፡በር፡ተከፍቶልኛልና፡ተቃዋሚዎችም፡ብዙ፡ናቸው ።

፲፤ ጢሞቴዎስም፡የመጣ፡እንደ፡ሆነ፡በእናንተ፡ዘንድ፡ያለ፡ፍርሃት፡እንዲኖር፡ተጠንቀቁ ፤ እንደ፡እኔ፡ደግሞ፡የጌታን፡ሥራ፡ይሠራልና ፤

፲፩፤ እንግዲህ፡ማንም፡አይናቀው ። ነገር፡ግን፡ከወንድሞቼ፡ጋር፡እጠብቀዋለሁና፡ወደ፡እኔ፡ይመጣ፡ዘንድ፡በሰላም፡በጕዞው፡እርዱት ።

፲፪፤ ስለ፡ወንድማችን፡ስለ፡አጵሎስ፡ግን፡ከወንድሞቼ፡ጋር፡ወደ፡እናንተ፡ሊሄድ፡እጅግ፡አድርጌ፡ለምኜው፡ነበር ፤ ዛሬም፡ለመምጣት፡ከቶ፡ፈቃድ፡አልነበረውም÷ሲመቸው፡ግን፡ይመጣል ።

፲፫፤ ንቁ÷በሃይማኖት፡ቁሙ÷ጐልምሱ፡ጠንክሩ ።

፲፬፤ በእናንተ፡ዘንድ፡ሁሉ፡በፍቅር፡ይሁን ።

፲፭፤ ወንድሞች፡ሆይ÷የእስጢፋኖስ፡ቤተ፡ሰዎች፡የአካይያ፡በኵራት፡እንደ፡ሆኑ፡ቅዱሳንንም፡ለማገልገል፡ራሳቸውን፡እንደ፡ሰጡ፡ታውቃላችሁ ፤

፲፮፤ እንደ፡እነርሱ፡ላሉትና፡አብሮ፡ለሚሠራ፡ለሚደክምም፡ሁሉ፡እናንተም፡እንድትገዙ፡እለምናችኋለሁ ።

፲፯፤ በእስጢፋኖስና፡በፈርዶናጥስ፡በአካይቆስም፡መምጣት፡ደስ፡ይለኛል÷እናንተ፡ስለሌላችሁ፡የጐደለኝን፡ፈጽመዋልና ፤

፲፰፤ መንፈሴንና፡መንፈሳችሁን፡አሳርፈዋልና ። እንግዲህ፡እንደነዚህ፡ያሉትን፡እወቁአቸው ።

፲፱፤ የእስያ፡አብያተ፡ክርስቲያናት፡ሰላምታ፡ያቀርቡላችኋል ። አቂላና፡ጵርስቅላ፡በቤታቸው፡ካለች፡ቤተ፡ክርስቲያን፡ጋር፡በጌታ፡እጅግ፡ሰላምታ፡ያቀርቡላችኋል ።

፳፤ ወንድሞች፡ሁሉ፡ሰላምታ፡ያቀርቡላችኋል ። በተቀደሰ፡አሳሳም፡እርስ፡በርሳችሁ፡ሰላምታ፡ተሰጣጡ ።

፳፩፤ እኔ፡ጳውሎስ፡ይህን፡ሰላምታ፡በገዛ፡እጄ፡ጽፌአለሁ ።

፳፪፤ ጌታን፡ኢየሱስ፡ክርስቶስን፡የማይወድ፡ቢኖር፡የተረገመ፡ይሁን ። ጌታችን፡ሆይ÷ና ።

፳፫፤ የጌታ፡የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ጸጋ፡ከእናንተ፡ጋር፡ይሁን ።

፳፬፤ ፍቅሬ፡በክርስቶስ፡ኢየሱስ፡ከሁላችሁ፡ጋር፡ነው ። አሜን ።

---

፲፭። ፶፩፡፶፪፤ ማቴ፡ ፳፬፡፴፩፤ ፩ተሰ፡ ፬፡፲፭—፲፯። ፶፫፤ ፪ቆሮ፡ ፭፡፬። ፶፬፤ ኢሳ፡ ፳፭፡፰። ፶፭፤ ሆሴ፡ ፲፫፡፲፬። ፶፮፤ ሮሜ ፯፡፲፫። ፶፯፤ ሮሜ ፰፡፴፯።

፲፮። ፩፤ የሐዋ፡ ፳፬፡፲፯፤ ፪ቆሮ፡ ፰፡፬። ፪፤ የሐዋ፡ ፳፡፯። ፭፤ የሐዋ፡ ፲፱፡፳፩። ፰፤ የሐዋ፡ ፲፱፡፩፡፲። ፱፤ የሐዋ፡ ፲፱፡፱፤ ራእ፡ ፫፡፰። ፲፤ ፊል፡ ፪፡፲፱። ፲፩፤ ፩ጢሞ፡ ፬፡፲፪። ፲፪፤ ፊል፡ ፩፡፳፯። ፲፫፤ ማቴ፡ ፳፬፡፵፪፤ ፩ቆሮ፡ ፬፡፪፤ ኤፌ፡ ፮፡፲። ፲፭፤ ፊል፡ ፩፡፳፯፤ ሮሜ ፲፮፡፭። ፲፯፤ ፩ተሰ፡ ፭፡፲፪። ፲፱፤ የሐዋ፡ ፲፰፡፪፡፲፰፡፳፮፤ ሮሜ ፲፮፡፫—፭። ፳፤ ሮሜ ፲፮፡፲፮። ፳፩፤ ፪ተሰ፡ ፫፡፲፯።

# ሁለተኛይቱ፡የሐዋርያው፡የጳውሎስ፡መልእክት፡ ወደ፡ቆሮንቶስ፡ሰዎች።

ምዕራፍ፡፩።

፩ በእግዚአብሔር፡ፈቃድ፡የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ሐዋርያ፡የሆነ፡ጳውሎስ፡ወንድሙም፡ጢሞቴዎስ፥ በአካይያ፡አገር፡ሁሉ፡ከሚኖሩ፡ቅዱሳን፡ሁሉ፡ጋር፡በቆሮንቶስ፡ላለች፡ለእግዚአብሔር፡ቤተ፡ክርስቲያን፤

፪ ከእግዚአብሔር፡ከአባታችን፡ከጌታም፡ከኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ጸጋና፡ሰላም፡ለእናንተ፡ይሁን።

፫ የርኅራኄ፡አባት፡የመጽናናትም፡ሁሉ፡አምላክ፡የሆነ፡የጌታችን፡የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ ፬ አምላክና፡አባት፡ይባረክ። እርሱ፡በመከራችን፡ሁሉ፡ያጽናናናል፥ ስለዚህም፡እኛ፡ራሳችን፡በእግዚአብሔር፡በምንጽናናበት፡መጽናናት፡በመከራ፡ሁሉ፡ያሉትን፡ማጽናናት፡ ፭ እንችላለን። የክርስቶስ፡ሥቃይ፡በእኛ፡ላይ፡እንደ፡በዛ፥ እንዲሁ፡መጽናናታችን፡ደግሞ፡ ፮ በክርስቶስ፡በኩል፡ይበዛልናልና። ዳሩ፡ግን፡መከራ፡ብንቀበል፥ ስለ፡መጽናናታችሁና፡ስለ፡መዳናችሁ፡ነው፤ ብንጽናናም፥ እኛ፡ደግሞ፡የምንሣቀይበት፡በዚያ፡ሥቃይ፡በመጽናት፡ስለሚደረግ፡ስለ፡መጽናናታችሁ፡ ፯ ነው። ተስፋችንም፡ስለ፡እናንተ፡ጽኑ፡ነው፤ ሥቃያችንን፡እንደ፡ተካፈላችሁ፡እንዲሁም፡መጽናናታችንን፡ደግሞ፡እንድትካፈሉ፡እናውቃለንና።

፰ በእስያ፡ስለ፡ደረሰብን፡መከራችን፥ ወንድሞች፡ሆይ፥ ታውቁ፡ዘንድ፡እንወዳለንና፤ ስለ፡ሕይወታችን፡እንኳ፡ተስፋ፡እስክንቈርጥ፡ድረስ፡ከዓቅማችን፡በላይ፡ያለ፡ልክ፡ከብዶብን፡ ፱ ነበር፤ አዎን፥ ሙታንን፡በሚያነሣ፡በእግዚአብሔር፡እንጂ፡በራሳችን፡እንዳንታመን፥ እኛ፡ራሳችን፡የሞትን፡ፍርድ፡በውስጣችን፡ ፲ ሰምተን፡ነበር። እርሱም፡ይህን፡ከሚያህል፡ሞት፡አዳነን፥ ያድነንማል፤ እናንተም፡ደግሞ፡ስለ፡እኛ፡እየጸለያችሁ፡አብራችሁ፡ስትረዱን፥ በብዙ፡ሰዎች፡በኩል፡ስለ፡ተሰጠን፡ስለ፡ጸጋ፡ስጦታ፡ብዙዎች፡ስለ፡እኛ፡ያመሰግኑ፡ዘንድ፥ ወደ፡ፊት፡ደግሞ፡እንዲያድን፡በእርሱ፡ተስፋ፡አድርገናል።

፲፪ ትምክህታችን፡ይህ፡ነውና፤ በእግዚአብሔር፡ጸጋ፡እንጂ፡በሥጋዊ፡ጥበብ፡ሳይሆን፥ በእግዚአብሔር፡ቅድስናና፡ቅንነት፡በዚህ፡ዓለም፡ይልቁንም፡በእናንተ፡ዘንድ፡እንደ፡ኖርን፡የሕሊናችን፡ምስክርነት፡ነው። ፲፫ ከምታነቡትና፡ከምታስተውሉት፡በቀር፡ሌላ፡እንጽፍላችሁምና፤ በጌታችንም፡በኢየሱስ፡ቀን፡እናንተ፡ደግሞ፡ትምክህታችን፡እንደምትሆኑ፡እንዲሁ፡ትምክህታችሁ፡እንድንሆን፥ በከፊል፡ስለ፡እኛ፡እንዳስተዋላችሁ፡ፈጽማችሁ፡ታስተውሉት፡ዘንድ፡ተስፋ፡አደርጋለሁ።

፲፭ በዚህም፡ታምኜ፥ ሁለተኛ፡ጸጋ፡ታገኙ፡ዘንድ፡አስቀድሜ፡ወደ፡እናንተ፡እንድመጣ፥ ፲፮ በእናንተም፡መካከል፡ወደ፡መቄዶንያ፡እንዳልፍ፡ደግሞም፡ከመቄዶንያ፡ወደ፡እናንተ፡መጥቼ፡ወደ፡ይሁዳ፡በጕዞዬ፡እንድትረዱኝ፡አሰብሁ። ፲፯ እንግዲህ፡ይህን፡ሳስብ፡ያን፡ጊዜ፡ቀሌትን፡አሳየሁን? ወይስ፡በእኔ፡ዘንድ፡አዎን፡አዎን፡አይደለም፡አይደለም፡ማለት፡እንዲሆን፡ያን፡የማስበው፡በዓለማዊ፡ልማድ፡ነውን? ፲፰ እግዚአብሔር፡ግን፡የታመነ፡ነው፥ ለእናንተም፡የሚነገረው፡ቃላችን፡አዎንና፡አይደለም፡አይሆንም። ፲፱ በእኛ፡ማለት፡በእኔና፡በስልዋኖስ፡በጢሞቴዎስም፡በመካከላችሁ፡የተሰበከ፡የእግዚአብሔር፡ልጅ፡ኢየሱስ፡ክርስቶስ፡አዎንና፡አይደለም፡አልነበረም፥ ነገር፡ግን፡በእርሱ፡አዎን፡ሆኖአል። ፳ እግዚአብሔር፡ስለሰጠው፡የተስፋ፡ቃል፡ሁሉ፡አዎን፡ማለት፡በእርሱ፡ነውና፥ ስለዚህ፡ለእግዚአብሔር፡ስለ፡ክብሩ፡በእኛ፡የሚነገረው፡አሜን፡በእርሱ፡ደግሞ፡ነው። ፳፩ በክርስቶስም፡ከእናንተ፡ጋር፡የሚያጸናንና፡የቀባን፡እግዚአብሔር፡ነው፥ ፳፪ ደግሞም፡ያተመን፡የመንፈሱንም፡መያዣ፡በልባችን፡የሰጠን፡እርሱ፡ነው።

፳፫ እኔ፡ግን፡ልራራላችሁ፡ስል፡እንደ፡ገና፡ወደ፡ቆሮንቶስ፡እንዳልመጣሁ፡በነፍሴ፡ላይ፡እግዚአብሔርን፡ምስክር፡እጠራለሁ። ፳፬ ለደስታችሁ፡ከእናንተ፡ጋር፡የምንሠራ፡ነን፡እንጂ፥ በእምነታችሁ፡በእናንተ፡ላይ፡የምንገዛ፡አይደለንም። በእምነታችሁ፡ቆማችኋልና።

ምዕራፍ፡፪።

፩ ነገር፡ግን፡ዳግመኛ፡በኀዘን፡ወደ፡እናንተ፡እንዳልመጣ፡ለእኔ፡ቈረጥሁ። ፪ እኔስ፡ባሳዝናችሁ፥ እንግዲያስ፡በእኔ፡ምክንያት፡ከሚያዝን፡በቀር፡ደስ፡የሚያሰኘኝ፡ማን፡ነው?

[illegible]

፫ ደስ፡ሊያሰኙኝ፡ከሚገባቸውም፡በመምጣቴ፡ ኀዘን፡እንዳይሆንብኝ፡ይህኑ፡ጻፍሁላችሁ÷ ደስታዬ፡የሁላችሁ፡ደስታ፡ነው፡ብዬ፡በሁላ
፬ ችሁ፡ታምኜአለሁና ። ስብዙ፡መከራና፡ከልብ፡ ጭንቀት፡በብዙም፡እንባ፡ጽፌላችሁ፡ነበርና ፤ ይህም፡እናንተን፡አብዝቼ፡የምወድበትን፡ ፍቅር፡እንድታውቁ፡እንጂ፡እንዳስዝናችሁ፡ አይደለም ።

፭ ነገር፡ግን፡ማንም፡አሳዝኖ፡ቢሆን÷እንዳ ልከብድብችሁ÷በክፍል፡ሁላችሁን፡እንጂ፡
፮ እኔን፡ያሳዘነ፡አይደለም ። እንደዚህ፡ላለ፡ ሰው፡ይህ፡ከእናንተ፡የምትበዙት፡የቀጣች
፯ ሁት፡ቅጣት፡ይበቃዋልና፡እንደዚህ፡ያለው፡ ከልክ፡በሚበዛ፡ኀዘን፡እንዳይዋጥ÷ይልቁ፡ ተመልሳችሁ፡ይቅር፡ማለትና፡ማጽናናት፡
፰ ይገባችኋል ። ስለዚህ፡ከእርሱ፡ጋር፡ፍቅርን፡
፱ እንድታጸኑ፡እለምናችኋለሁ ፤ ስለዚህ፡ደግሞ፡ ጽፌ፡ነበርና ፤ በሁሉ፡የምትታዘዙ፡እንደ፡ ሆናችሁ፡የእናንተን፡መፈተን፡አውቅ፡ዘንድ፡
፲ አሳቤ፡ነበር ። እናንተ፡ግን፡ይቅር፡የምትሉ ትን፡እኔ፡ደግሞ፡ይቅር፡እለዋለሁ ፤ እኔም፡ ይቅር፡ካልሁ÷ይቅር፡ያልሁትን፡ስለ፡እና
፲፩ ንተ፡በክርስቶስ፡ፊት፡ይቅር፡ብዬአለሁ÷በሰ ይጣን፡እንዳንታለል ፤ የእርሱን፡አሳብ፡አን ስተውምና ።

፲፪ ስለ፡ክርስቶስም፡ወንጌል፡ወደ፡ጢሮአዳ፡ በመጣሁ፡ጊዜ÷ለጌታ፡ሥራ፡በር፡ምንም፡
፲፫ ቢከፈትልኝ÷ቲቶን፡ወንድሜን፡ስላላገኘሁት፡ መንፈሴ፡ዕረፍት፡አልነበረውም÷ነገር፡ግን፡ ከእነርሱ፡ተሰናብቼ፡ወደ፡መቄዶንያ፡ወጣሁ ።

፲፬ ነገር፡ግን፡በክርስቶስ፡ሁልጊዜ፡ድል፡በመ ንሣቱ፡ለሚያዞረን፡በእኛም፡በየስፍራው፡ ሁሉ፡የእውቀቱን፡ሽታ፡ለሚገልጥ፡ለእግዚ
፲፭ አብሔር፡ምስጋና፡ይሁን ፤ በሚድኑቱና፡በሚ ጠፉቱ፡ዘንድ፡ለእግዚአብሔር፡የክርስቶስ፡
፲፮ መዓዛ፡ነንና ፤ ለእነዚህ፡ለሞት፡የሚሆን፡ የሞት፡ሽታ፡ለእነዚያም፡ለሕይወት፡የሚሆን፡ የሕይወት፡ሽታ፡ነን ። ለዚህም፡ነገር፡የሚ
፲፯ በቃ፡ማን፡ነው ? የእግዚአብሔርን፡ቃል፡ ቀላቅለው፡እንደሚሸቃቅጡት፡እንደ፡ብዙ ዎቹ፡አይደለንምና ፤ በቅንነት፡ግን፡ከእግዚ አብሔር፡እንደ፡ተላክን፡በእግዚአብሔር፡ ፊት፡በክርስቶስ፡ሆነን፡እንናገራለን ።

## ምዕራፍ፡፫ ።

፩ እንደ፡ገና፡ራሳችንን፡ልናመሰግን፡እንጀ ምራለንን ? ወይስ፡እንደ፡ሌሎች፡የማመስ
፪ ገኛ፡መልእክት፡ወደ፡እናንተ፡ወይስ፡ከእና ንተ፡ያስፈልገን፡ይሆንን ? ሰዎች፡ሁሉ፡የሚ ያውቁትና፡የሚያነቡት፡በልባችን፡የተጻፈ፡
፫ መልእክታችን፡እናንተ፡ናችሁ ። እናንተም፡ በሕያው፡እግዚአብሔር፡መንፈስ፡እንጂ፡በቀ ለም፡አይደለም÷ሥጋ፡በሆነ፡በልብ፡ጽላት፡ እንጂ፡በድንጋይ፡ጽላት፡ያልተጻፈ÷በእኛም፡ የተገለገለ፡የክርስቶስ፡መልእክት፡እንደ፡ሆና ችሁ፡የተገለጠ፡ነው ።

፬ በክርስቶስም፡በኩል፡ወደ፡እግዚአብሔር፡
፭ እንዲህ፡ያለ፡እምነት፡አለን ። ብቃታችን፡ ከእግዚአብሔር፡ነው፡እንጂ÷በገዛ፡እጃችን፡ እንደሚሆን፡አንዳችን፡እንኳ፡ልናስብ፡ራስ
፮ ችን፡የበቃን፡አይደለንም ፤ እርሱም፡ደግሞ፡ በመንፈስ፡እንጂ፡በፊደል፡ለማይሆን፡ለአ ዲስ፡ኪዳን፡አገልጋዮች፡እንሆን፡ዘንድ፡አበ ቃን ፤ ፊደል፡ይገድላልና፡መንፈስ፡ግን፡ሕይ ወትን፡ይሰጣል ።

፯ ዳሩ፡ግን፡የእስራኤል፡ልጆች፡ስለዚያ፡ ስለ፡ተሻረው፡ስለ፡ፊቱ፡ክብር፡የሙሴን፡ፊት፡ ትኵር፡ብለው፡መመልከት፡እስኪሳናቸው፡ ድረስ÷ያ፡በፊደላት፡በድንጋዮች፡ላይ፡የተ ቀረጸ፡የሞት፡አገልግሎት፡በክብር፡ከሆነ÷
፰ የመንፈስ፡አገልግሎት፡እንዴት፡ይልቁ፡በክ
፱ ብር፡አይሆንም ? የኵነኔ፡አገልግሎት፡ክብር፡ ከሆነ÷ይልቁ፡የጽድቅ፡አገልግሎት፡በክብር፡
፲ እብዝቶ፡ይበልጣልና ። ያ፡የከበረ፡እንኳ፡ እጅግ፡በሚበልጠው፡ክብር፡ምክንያት፡በዚህ፡
፲፩ ነገር፡ክብሩን፡አጥቶአልና ። ያ፡ይሻር፡የነ በረው፡በክብር፡ከሆነ÷ጸንቶ፡የሚኖረውማ፡ እጅግ፡ይልቅ፡በክብር፡ሆኖአልና ።

፲፪ እንግዲህ፡እንዲህ፡ያለ፡ተስፋ፡ካለን፡እጅግ፡
፲፫ ግልጠን፡እንናገራለን÷የዚያንም፡ይሻር፡የነ በረውን፡መጨረሻ፡ትኵር፡ብለው፡የእስራ ኤል፡ልጆች፡እንዳይመለከቱ÷በፊቱ፡መጋ ረጃ፡እንዳደረገ፡እንደ፡ሙሴ፡አይደለንም ።
፲፬ ነገር፡ግን፡አሳባቸው፡ደነዘዘ ። ብሉይ፡ኪዳን፡ ሲነበብ፡ያ፡መጋረጃ፡ሳይወሰድ፡እስከ፡ዛሬ፡ ድረስ፡ይኖራልና ፤ በክርስቶስ፡ብቻ፡የተ
፲፭ ሻረ፡ነውና ። ነገር፡ግን፡እስከ፡ዛሬ፡ድረስ፡ የሙሴ፡መጻሕፍት፡በተነበቡ፡ጊዜ፡ሁሉ፡
፲፮ ያ፡መጋረጃ፡በልባቸው፡ይኖራል ፤ ወደ፡ጌታ፡ ግን፡በዞር፡ባለ፡ጊዜ፡ሁሉ፡መጋረጃው፡
፲፯ ይወሰዳል ። ጌታ፡ግን፡መንፈስ፡ነው ፤ የጌ ታም፡መንፈስ፡ባለበት፡በዚያ፡አርነት፡አለ ።
፲፰ እኛም፡ሁላችን፡በመጋረጃ፡በማይከደን፡ፊት፡ የጌታን፡ክብር፡እንደ፡መስተዋት፡እያብለጨ ለጭን፡መንፈስ፡ከሚሆን፡ጌታ፡እንደሚደ ረግ፡ያን፡መልክ፡እንመስል፡ዘንድ፡ከክብር፡ ወደ፡ክብር፡እንለወጣለን ።

፪። ፭፤ ፩ ቆሮ. ፭፥፩፡፪። ፮፤ ፩ ቆሮ. ፭፥፬፡፭። ፯፤ ገላ. ፮፥፩። ፲፪፡፲፫፤ ሥራ. ፲፮፥፰፤ ቲቶ ፩፥፬፤ የሐዋ. ፳፥ ፩። ፲፮፤ ሥራ. ፫፥፭፡፯። ፲፯፤ ሥራ. ፲፥፲፱።
፫። ፩፤ የሐዋ. ፲፰፥፳፯። ፪፤ ፩ ቆሮ. ፱፥፪። ፫፤ ዘፀአ. ፳፬፥፲፪፤ ኤር. ፴፩፥፴፫። ፭፤ ፩ ቆሮ. ፲፭፥፲። ፯፤ ኤር. ፴፩፥፴፩፤ ሮሜ ፯፥፮፤ ዮሐ. ፮፥፷፫። ፯፤ ዘፀአ. ፴፬፥፴፤ ፴፭። ፲፫፤ ዘፀአ. ፴፬፥፴፫፤ ፴፭። ፲፬፤ ሮሜ ፲፩፥፯፤ ፰፥ ፲፮፤ ዘፀአ. ፴፬፥፴፬። ፲፯፤ ገላ. ፬፥፮፤ ፯፤ ዮሐ. ፳፥፴፩።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ፡

፩ ስለዚህ ፡ ምክንያት ፡ ምሕረት ፡ እንደ ፡ ተሰ ጠን ፡ መጠን ፡ ይህ ፡ አገልግሎት ፡ ስላለን ፡ አን ታክትም ፡ ፪ ነገር ፡ ግን ፡ የሚያስፍረውን ፡ ስውር ፡ ነገር ፡ ጥለናልና ፡ በተንኰል ፡ አንመላለስም ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ቃል ፡ በውሸት ፡ አንቀላ ቅልም ፤ እውነትን ፡ በመግለጥ ፡ ግን ፡ በእግዚ አብሔር ፡ ፊት ፡ ለሰው ፡ ሕሊና ፡ ሁሉ ፡ ራሳች ንን ፡ እናመሰግናለን ፡ ፫ ወንጌላችን ፡ የተከደነ ፡ ቢሆን ፡ እንኳ ፡ የተከደነባቸው ፡ ለሚጠፉ ፡ ነው ፡ ፬ ለእነርሱም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ምሳሌ ፡ የሆነ ፡ የክርስቶስ ፡ የክብሩ ፡ ወንጌል ፡ ብርሃን ፡ እንዳ ያበራላቸው ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ አምላክ ፡ የማያም ኑትን ፡ አሳብ ፡ አሳወረ ፡ ፭ ክርስቶስ ፡ ኢየሱስን ፡ ጌታ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንጂ ፡ ራሳችንን ፡ እንሰብክ ምና ፡ ስለ ፡ ኢየሱስም ፡ ራሳችንን ፡ ለእናንተ ፡ ባሪያዎች ፡ እናደርጋለን ፡ ፮ በክርስቶስ ፡ ፊት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የክብሩን ፡ እውቀት ፡ ብርሃን ፡ እንዲሰጥ ፡ በልባችን ፡ ውስጥ ፡ የበራ ፥— በጨ ለማ ፡ ብርሃን ፡ ይብራ ፡ ያለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነውና ፡

፯ ነገር ፡ ግን ፡ የኃይሉ ፡ ታላቅነት ፡ ከእግዚአብ ሔር ፡ እንጂ ፡ ከእኛ ፡ እንዳይሆን ፡ ይህ ፡ መዝ ገብ ፡ በሸክላ ፡ ዕቃ ፡ ውስጥ ፡ አለን ፤ ፰ በሁሉ ፡ እንገፋለን ፡ እንጂ ፡ አንጨነቅም ፤ እናመነታ ለን ፡ እንጂ ፡ ተስፋ ፡ አንቈርጥም ፤ ፱ እንሰደዳ ለን ፡ እንጂ ፡ አንጣልም ፤ እንወድቃለን ፡ እንጂ ፡ አንጠፋም ፤ ፲ የኢየሱስ ፡ ሕይወት ፡ ደግሞ ፡ በሥ ጋችን ፡ ይገለጥ ፡ ዘንድ ፡ ሁልጊዜ ፡ የኢየሱስን ፡ መሞት ፡ በሥጋችን ፡ ተሸክመን ፡ እንዞራለን ፡ ፲፩ የኢየሱስ ፡ ሕይወት ፡ ደግሞ ፡ በሚሞት ፡ ሥጋ ችን ፡ ይገለጥ ፡ ዘንድ ፡ እኛ ፡ ሕያዋን ፡ የሆንን ፡ ከኢየሱስ ፡ የተነሣ ፡ ዘወትር ፡ ለሞት ፡ አልፈን ፡ እንሰጣለንና ፡ ፲፪ ስለዚህ ፡ ሞቱ ፡ በእኛ ፡ ሕይወ ቱም ፡ በእናንተ ፡ ይሠራል ፡

፲፫ ነገር ፡ ግን ፡— አመንሁ ፡ ስለዚህም ፡ ተናገ ርሁ ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ያው ፡ አንዱ ፡ የእ ምነት ፡ መንፈስ ፡ ስላለን ፥ እኛ ፡ ደግሞ ፡ እናም ናለን ፡ ስለዚህም ፡ እንናገራለን ፤ ፲፬ ጌታን ፡ ኢየ ሱስን ፡ ያስነሣው ፡ እኛን ፡ ደግሞ ፡ ከኢየሱስ ፡ ጋር ፡ እንዲያስነሣን ፡ ከእናንተም ፡ ጋር ፡ እንዲ ያቀርበን ፡ እናውቃለንና ፡ ፲፭ በብዙዎች ፡ ስኩል ፡ የተትረፈረፈው ፡ ጸጋ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ ምስጋናን ፡ ያበዛ ፡ ዘንድ ፥ ሁሉ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ነውና ፡

፲፮ ስለዚህም ፡ አንታክትም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ የው ጭው ፡ ሰውነታችን ፡ ቢጠፋ ፡ እንኳ ፡ የው ስጡ ፡ ሰውነታችን ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ይታደሳል ፡ ፲፯፡፲፰ የማይታየውን ፡ እንጂ ፡ የሚታየውን ፡ በንመለ ከት ፥ ቀላል ፡ የሆነ ፡ የጊዜው ፡ መከራችን ፡ የክ ብርን ፡ የዘላለም ፡ ብዛት ፡ ከሁሉ ፡ መጠን ፡ ይልቅ ፡ ያደርግልናልና ፤ የሚታየው ፡ የጊዜው ፡ ነውና ፥ የማይታየው ፡ ግን ፡ የዘላለም ፡ ነው ፡

## ምዕራፍ ፡ ፭ ፡

፩ ድንኳን ፡ የሚሆነው ፡ ምድራዊ ፡ መኖሪያችን ፡ ቢፈርስ ፥ በሰማይ ፡ ያለ ፡ በእጅ ፡ ያልተሠራ ፡ የዘላለም ፡ ቤት ፡ የሚሆን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የተ ሠራ ፡ ሕንጻ ፡ እንዳለን ፡ እናውቃለንና ፡ ፪ በዚህ ፡ ውስጥ ፡ በእውነት ፡ እንቃትታለንና ፥ ከሰማይም ፡ የሚሆነውን ፡ መኖሪያችንን ፡ እንድንለብስ ፡ እን ናፍቃለንና ፡ ፫ ለብሰን ፡ ራቁታችንን ፡ አንገኝም ፡ ፬ በእውነትም ፡ የሚሞተው ፡ በሕይወት ፡ ይዋጥ ፡ ዘንድ ፡ ልንለብስ ፡ እንጂ ፡ ልንገፈፍ ፡ የማንወድ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፥ በድንኳኑ ፡ ያለን ፡ እኛ ፡ ከብደን ፡ እን ቃትታለን ፡ ፭ ነገር ፡ ግን ፡ ለዚሁ ፡ የሠራን ፡ እግዚ አብሔር ፡ ነው ፡ እርሱም ፡ የመንፈሱን ፡ መያዣ ፡ ሰጠን ፡

፮፡፯ ከንግዲህ ፡ ሁልጊዜ ፡ ታምነን ፥ በእምነት ፡ እንጂ ፡ በማየት ፡ አንመላለስምና ፡ በሥጋ ፡ ስና ድር ፡ ከጌታ ፡ ተለይተን ፡ በስደት ፡ እንዳለን ፡ የምናውቅ ፡ ከሆንን ፥ ታምነናል ፡ ፰ ይልቁንም ፡ ከሥጋ ፡ ተለይተን ፡ በስደት ፡ መኖር ፡ በጌታም ፡ ዘንድ ፡ ማደር ፡ ደስ ፡ ይለናል ፡ ፱ ስለዚህ ፡ ደግሞ ፡ ብናድር ፡ ወይም ፡ ተለይተን ፡ ብንሆን ፡ እርሱን ፡ ደስ ፡ የምናሰኝ ፡ ልንሆን ፡ እንቀናለን ፡ ፲ መል ካም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ክፉ ፡ እንዳደረገ ፥ እያን ዳንዱ ፡ በሥጋው ፡ የተሠራውን ፡ በብድራት ፡ ይቀበል ፡ ዘንድ ፡ ሁላችን ፡ በክርስቶስ ፡ በፍርድ ፡ ወንበር ፡ ፊት ፡ ልንገለጥ ፡ ይገባናልና ፡

፲፩ እንግዲህ ፡ የጌታን ፡ ፍርሃት ፡ አውቀን ፡ ሰዎ ችን ፡ እናስረዳለን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ግን ፡ የተ ገለጥን ፡ ነን ፤ በሕሊናችሁም ፡ ደግሞ ፡ የተገለ ጥን ፡ እንደ ፡ ሆንን ፡ ተስፋ ፡ አደርጋለሁ ፡ ፲፪ በመ ልክ ፡ እንጂ ፡ በልብ ፡ ለማይመኩ ፡ የምትመል ሱላቸው ፡ መልስ ፡ እንዲኖራችሁ ፥ በእኛ ፡ ልት መኩ ፡ ምክንያት ፡ እንሰጣችኋለን ፡ እንጂ ፡ ራስ ችንን ፡ ደግሞ ፡ ለእናንተ ፡ የምናመሰግን ፡ አይ ደለንም ፡ ፲፫ እብዶች ፡ ብንሆን ፥ ለእግዚአብሔር ፡ ነው ፤ ባለ ፡ አእምሮዎች ፡ ብንሆን ፥ ለእናንተ ፡ ነው ፡ ፲፬ ይህን ፡ ስለ ፡ ቈረጥን ፡ የክርስቶስ ፡ ፍቅር ፡ ግድ ፡ ይለናልና ፤ አንዱ ፡ ስለ ፡ ሁሉ ፡ ሞተ ፤ እን ግዲያስ ፡ ሁሉ ፡ ሞቱ ፤ ፲፭ በሕይወትም ፡ ያሉት ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ ስለሞተውና ፡ ስለተነሣው ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ለራሳቸው ፡ እንዳይኖሩ ፡ ስለ ፡ ሁሉ ፡ ሞተ ፡

፲፮ ስለዚህ ፡ እኛ ፡ ከአሁን ፡ጀምሮ ፡ ማንንም ፡ በሥጋ ፡ እንደሚሆን ፡ አናውቅም ፤ ክርስቶስ

---

፬። ፪፤ ም. ፩ ፥ ፲፱ ፤ ፩ ተሰ. ፪ ፥ ፭። ፫፤ ዮሐ. ፲፪ ፥ ፴፩ ፤ ቈላ. ፩ ፥ ፲፭። ፭፤ ፩ ቆሮ. ፱ ፥ ፲፱። ፮፤ ዘፍጥ. ፩ ፥ ፫። ፯፤ ፩ ቆሮ. ፪ ፥ ፭። ፱፤ መዝ. ፴፯ ፥ ፳፬። ፲ ፡ ፲፩፤ ሮሜ ፰ ፥ ፴፮ ፤ ፩ ቆሮ. ፲፭ ፥ ፴፩። ፲፫፤ መዝ. ፻፲፮ ፥ ፩። ፲፬፤ ፩ ቆሮ. ፮ ፥ ፲፬። ፲፭፤ ኤፌ. ፫ ፥ ፲፫። ፲፯፤ ሮሜ ፰ ፥ ፲፰።

፭። ፩፤ ዮሐ. ፲፬ ፥ ፪። ፪፤ ሮሜ ፰ ፥ ፳፫። ፬፤ ፩ ቆሮ. ፲፭ ፥ ፶፫። ፮፤ ም. ፩ ፥ ፳፪። ፰፤ ፊልጵ. ፩ ፥ ፳፫። ፲፤ ሮሜ ፪ ፥ ፮ ፤ ፲፬ ፥ ፲። ፲፩፤ ዕብ. ፲ ፥ ፴፩። ፲፫፤ የሐዋ. ፳፮ ፥ ፳፬። ፲፭፤ ሮሜ ፲፬ ፥ ፯ ፡ ፰።

ንም ፡ በሥጋ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያወቅነው ፡ ብንሆን ፡
እንኳ ÷ አሁን ፡ ግን ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ እን
፲፯ ደዚህ ፡ አናውቀውም ። ስለዚህ ፡ ማንም ፡ በክር
ስቶስ ፡ ቢሆን ፡ አዲስ ፡ ፍጥረት ፡ ነው ፤ አሮጌው ፡
ነገር ፡ አልፎአል ፤ እነሆ ÷ ሁሉም ፡ አዲስ ፡ ሆኖ
፲፰ አል ። ነገር ፡ ግን ፡ የሆነው ፡ ሁሉ ÷ በክርስቶስ ፡
ከራሱ ፡ ጋር ፡ ካስታረቀን ፡ የማስታረቅም ፡ አገል
፲፱ ግሎት ፡ ከሰጠን ÷ ከእግዚአብሔር ፡ ነው ፤ እግዚ
አብሔር ፡ በክርስቶስ ፡ ሆኖ ፡ ዓለሙን ፡ ከራሱ ፡
ጋር ፡ ያስታርቅ ፡ ነበርና ÷ በደላቸውን ፡ አይቈ
ጥርባቸውም ፡ ነበር ፤ በእኛም ፡ የማስታረቅ ፡
፳ ቃል ፡ አኖረ ። እንግዲህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእኛ ፡
እንደሚማልድ ፡ ስለ ፡ ክርስቶስ ፡ መልክተኞች ፡
ነን ፤ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ ታረቁ ፡ ብለን ፡
፳፩ ስለ ፡ ክርስቶስ ፡ እንለምናለን ። እኛ ፡ በእርሱ ፡
ሆነን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጽድቅ ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ፡
ኃጢአት ፡ ያላወቀውን ፡ እርሱን ፡ ስለ ፡ እኛ ፡
ኃጢአት ፡ አደረገው ።

ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ አብረንም ፡ እየሠራን ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ጸጋ ፡ በከንቱ ፡ እንዳትቀበሉ ፡ ደግሞ ፡ እንለም
ናለን ፤
፪ በተወደደ ፡ ሰዓት ፡ ሰማሁህ ፡ በመዳንም ፡
ቀን ፡ ረዳሁህ ፡
ይላልና ፤ እነሆ ÷ የተወደደው ፡ ሰዓት ፡ አሁን ፡
ነው ፤ እነሆ ÷ የመዳን ፡ ቀን ፡ አሁን ፡ ነው ።
፫ አገልግሎታችንም ፡ እንዳይነቀፍ ፡ በአንዳች ፡
፬ ነገር ፡ ማሰናከያ ፡ ከቶ ፡ አንሰጥም ። ነገር ፡ ግን ፡
በሁሉ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አገልጋዮች ፡
ራሳችንን ፡ እናማጥናለን ፤ በብዙ ፡ መጽናት ÷
፭ በመከራ ÷ በችግር ÷ በጭንቀት ÷ በመገረፍ ÷
በወኅኒ ÷ በሁከት ÷ በድካም ÷ እንቅልፍ ፡ በማ
፮ ጣት ÷ በመጦም ÷ በንጽሕና ÷ በእውቀት ÷ በት
ዕግሥት ÷ በቸርነት ÷ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ÷ ግብ
፯ ዝነት ፡ በሌለው ፡ ፍቅር ÷ በእውነት ፡ ቃል ÷ በእ
ግዚአብሔር ፡ ኃይል ÷ ስቀኝና ፡ ለግራ ፡ በሚ
፰ ሆን ፡ በጽድቅ ፡ የጦር ፡ ዕቃ ÷ በክብርና ፡ በው
ርደት ÷ በክፉ ፡ ወሬና ፡ በመልካም ፡ ወሬ ፡ ራሳ
ችንን ፡ እናማጥናለን ፤ አሳቾች ፡ ስንባል ፡ እው
፱ ነተኞች ፡ ነን ፤ ያልታወቁ ፡ ስንባል ፡ የታወቅን ፡
ነን ፤ የምንሞት ፡ ስንመስል ፡ እነሆ ፡ ሕያዋን ፡
፲ ነን ፤ የተቀጣን ፡ ስንሆን ፡ አንገደልም ፤ ኀዘንተ
ኞች ፡ ስንሆን ፡ ዘወትር ፡ ደስ ፡ ይለናል ፤ ድሆች ፡
ስንሆን ፡ ብዙዎችን ፡ ባለ ፡ ጠጎች ፡ እናደርጋለን ፤
አንዳች ፡ የሌለን ፡ ስንሆን ፡ ሁሉ ፡ የእኛ ፡ ነው ።
፲፩ እናንተ ፡ የቆሮንቶስ ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ÷ አፋችን ፡
ለእናንተ ፡ ተከፍቶአል ፡ ልባችንም ፡ ሰፍቶላች
፲፪ ኋል ፤ በእኛ ፡ አልጠበባችሁም ፡ በሆዳችሁ ፡
፲፫ ግን ፡ ጠበባችኋል ፤ ልጆቼ ፡ እንደ ፡ መሆናችሁ ፡
ግን ፡ እላችኋለሁ ÷ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ብድራት ፡
መልሳችሁልን ፡ ተከፈቱ ።
፲፬ ከማያምኑ ፡ ጋር ፡ በማይመች ፡ አካሄድ ፡ አት
ጠመዱ ፤ ጽድቅ ፡ ከዓመፅ ፡ ጋር ፡ ምን ፡ ተካፋ
ይነት ፡ አለውና ? ብርሃንም ፡ ከጨለማ ፡ ጋር ፡
፲፭ ምን ፡ ኅብረት ፡ አለው ? ክርስቶስስ ፡ ከቤልሆር ፡
ጋር ፡ ምን ፡ መስማማት ፡ አለው ? ወይስ ፡ የሚ
ያምን ፡ ከማያምን ፡ ጋር ፡ ምን ፡ ክፍል ፡ አለው ?
፲፮ ለእግዚአብሔር ፡ ቤተ ፡ መቅደስም ፡ ከጣዖት ፡
ጋር ፡ ምን ፡ መጋጠም ፡ አለው ? እኛ ፡ የሕያው ፡
እግዚአብሔር ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ነንና ፤ እንዲ
ሁም ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናገረ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡—
በእነርሱ ፡ እኖራለሁ ፡ በመካከላቸውም ፡
እመላለሳለሁ ÷ አምላካቸውም ፡ እሆናለሁ ፡
እነርሱም ፡ ሕዝቤ ፡ ይሆናሉ ።
፲፯፡፲፰ ስለዚህም ፡ ጌታ ፡—
ከመካከላቸው ፡ ውጡና ፡ የተለያችሁ ፡ ሁኑ ፡
ርኵስንም ፡ አትንኩ ፡
ይላል ፤ ሁሉንም ፡ የሚገዛ ፡ ጌታ ፡—
እኔም ፡ እቀበላችኋለሁ ÷ ለእናንተም ፡ አባት ፡
እሆናለሁ ፡ እናንተም ፡ ለእኔ ፡ ወንድ ፡ ልጆ
ችና ፡ ሴት ፡ ልጆች ፡ ትሆናላችሁ ፡
ይላል ።

ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ እንግዲህ ÷ ወዳጆች ፡ ሆይ ÷ የዚህ ፡ ተስፋ ፡
ቃል ፡ ካለን ÷ በእግዚአብሔር ፡ ፍርሃት ፡ ቅድ
ስናን ፡ ፍጹም ፡ እያደረግን ፡ ሥጋንና ፡ መንፈ
ስን ፡ ከሚያረክስ ፡ ሁሉ ፡ ራሳችንን ፡ እናንጻ ።
፪ በልባችሁ ፡ ስፍራ ፡ አስፉልን ፤ ማንንም ፡
አልበደልንም ÷ ማንንም ፡ አላጠፋንም ÷ ማን
፫ ንም ፡ አላታለልንም ። ለኵነኔ ፡ አልልም ፤ በአ
ንድነት ፡ ለመሞትና ፡ በአንድነት ፡ ለመኖር ፡
በልባችን ፡ እንዳላችሁ ፡ አስቀድሜ ፡ ብዬአለ
፬ ሁና ። ስለ ፡ እናንተ ፡ እምነቴ ፡ ታላቅ ፡ ነው ÷
በእናንተ ፡ ምክንያት ፡ ትምክህቴ ፡ ታላቅ ፡ ነው ፤
መጽናናት ፡ ሞልቶብኛል ፤ በመከራችን ፡ ሁሉ ፡
ደስታዬ ፡ ከመጠን ፡ ይልቅ ፡ ይበዛል ።
፭ ወደ ፡ መቄዶንያም ፡ በመጣን ፡ ጊዜ ÷ በሁሉ ፡
ነገር ፡ መከራን ፡ ተቀበልን ፡ እንጂ ፡ ሥጋችን ፡
ዕረፍት ፡ አልነበረውም ፤ በውጭ ፡ ጠብ ፡ ነበረ ÷
፮ በውስጥ ፡ ፍርሃት ፡ ነበረ ። ነገር ፡ ግን ፡ ኀዘንተ
ኞችን ፡ የሚያጽናና ፡ አምላክ ፡ በቲቶ ፡ መም
፯ ጣት ፡ አጽናናን ፤ በመምጣቱም ፡ ብቻ ፡ አይደ
ለም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ናፍቆታችሁንና ፡ ልቅሶአች
ሁን ፡ ስለ ፡ እኔም ፡ ቅንዓታችሁን ፡ ሲናገረን ፡ በእ
ናንተ ፡ ላይ ፡ በተጽናናበት ፡ መጽናናት ፡ ደግሞ ፡
ነው ፤ ስለዚህም ፡ ከፊት ፡ ይልቅ ፡ ደስ ፡ አለን ።

፭። ፲፯ ፤ ቈላ. ፫ ፡ ፱ ፡ ፲ ። ፲፰ ፡ ፲፱ ፤ ሮሜ. ፭ ፡ ፲ ፡ ፲፩ ። ፳፩ ፤ ፩ ጴጥ. ፪ ፡ ፳፪ ፡ ፳፬ ፤ ገላ. ፫ ፡ ፲፫ ፤ ሮሜ. ፰ ፡ ፫ ።
፮። ፪ ፤ ኢሳ. ፵፱ ፡ ፰ ። ፬ ፤ ምዕ. ፲፪ ፡ ፲ ። ፭ ፤ ምዕ. ፲፩ ፡ ፳፫ ፡ ፳፯ ። ፮ ፤ ፩ ጢሞ. ፬ ፡ ፲፪ ። ፯ ፤ ፩ ቆሮ. ፪ ፡ ፬ ። ፱ ፤ ምዕ. ፬ ፡ ፲ ፡ ፲፩ ፡ መዝ. ፻፲፰ ፡ ፲፰ ። ፲ ፤ ሮሜ. ፰ ፡ ፴፪ ። ፲፬ ፤ ዘዳግ. ፯ ፡ ፫ ፡ ኤፌ. ፭ ፡ ፯ ፡ ፲፩ ። ፲፮ ፤ ፩ ቆሮ. ፫ ፡ ፲፮ ፡ ዘሌዋ. ፳፮ ፡ ፲፪ ። ፲፯ ፤ ኢሳ. ፶፪ ፡ ፲፩ ። ፲፰ ፤ ፪ ሳሙ. ፯ ፡ ፲፬ ፡ ኤር. ፴፩ ፡ ፱ ፡ ፴፫ ።
፯። ፪ ፤ ምዕ. ፲፪ ፡ ፲፯ ። ፭ ፤ ምዕ. ፪ ፡ ፲፫ ። ፯ ፤ ምዕ. ፮ ፡ ፲፩ ።

፰፤ በመልእክቴ፡ያስዘንኋችሁ፡ብሆን፡እንኳ፡አል
ጸጸትም፤የተጸጸትሁ፡ብሆን፡እንኳ፥ያ፡መል
እክት፡ጥቂት፡ጊዜ፡ብቻ፡እንዳሳዘናችሁ፡
፱፤ አያለሁና፡አሁን፡ስንስሐ፡ስላዘናችሁ፡ደስ፡
ብሎኛል፡እንጂ፡ስላዘናችሁ፡አይደለም፤በም
ንም፡ከእኛ፡የተነሣ፡እንዳትጐዱ፡እንደ፡እግ
፲፤ ዚአብሔር፡ፈቃድ፡አዝናችኋልና ። እንደ፡
እግዚአብሔር፡ፈቃድ፡የሆነ፡ኀዘን፡ጸጸት፡
የሌለበትን፥ወደ፡መዳንም፡የሚያደርሰውን፡
ንስሐ፡ያደርጋልና፤የዓለም፡ኀዘን፡ግን፡
፲፩፤ ሞትን፡ያመጣል ። እነሆ፥ይህ፡እንደ፡እግዚ
አብሔር፡ፈቃድ፡የሆነ፡ኀዘን፡እንዴት፡ያለ፡
ትጋት፥እንዴት፡ያለ፡መልስ፥እንዴት፡ያለ፡
ቍጣ፥እንዴት፡ያለ፡ፍርሃት፥እንዴት፡ያለ፡
ናፍቆት፥እንዴት፡ያለ፡ቅንዓት፥እንዴት፡
ያለ፡በቀል፡በመካከላችሁ፡አደረገ ። በዚህ፡
ነገር፡ንጹሐን፡እንደ፡ሆናችሁ፡በሁሉ፡አስረድ
፲፪፤ ታችኋል ። እንግዲያስ፡የጻፍሁላችሁ፡ብሆን፡
እንኳ፥ስለ፡እኛ፡ያላችሁ፡ትጋታችሁ፡ከእ
ናንተ፡ዘንድ፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡እንዲገ
ለጥ፡እንጂ፥ስለ፡በዳዩ፡ወይም፡ስለ፡ተበ
፲፫፤ ዳዩ፡አልጻፍሁም ። ስለዚህ፡ተጽናንተናል ።
በመጽናናታችንም፡ስለ፡ቲቶ፡ደስታ፡አብ
ልጦ፡ደስ፡አለን፥መንፈሱ፡በሁላችሁ፡ዐር
፲፬፤ ፎአልና፤ለእርሱ፡በምንም፡ስለ፡እናንተ፡
የተመካሁ፡እንደ፡ሆነ፡አላፈርሁምና፥ነገር፡
ግን፡ሁሉን፡ለእናንተ፡በእውነት፡እንደ፡ተናገ
ርን፥እንደዚሁ፡ደግሞ፡ትምክህታችን፡በቲቶ፡
፲፭፤ ፊት፡እውነት፡ሆነ ። ስለዚህም፡በፍርሃትና፡
በመንቀጥቀጥ፡እንዴት፡እንደ፡ተቀበላችሁት፥
የሁላችሁን፡መታዘዝ፡እያሰበ፡ፍቅሩ፡በእና
፲፮፤ ንተ፡ላይ፡እጅግ፡በዝቶአል ። በነገር፡ሁሉ፡
ተማምኜባችኋለሁና፡ደስ፡ይለኛል ።

## ምዕራፍ፡፰ ።

፩፤ ወንድሞች፡ሆይ፥ለመቄዶንያ፡አብያተ፡
ክርስቲያናት፡የተሰጠውን፡የእግዚአብሔርን፡
፪፤ ጸጋ፡እናስታውቃችኋለን፤በብዙ፡መከራ፡
ተፈትነው፡ሳሉ፡የደስታቸው፡ብዛትና፡የድህ
ነታቸው፡ጥልቅነት፡የልግስናቸውን፡ባለ፡ጠግ
፫፤ ነት፡አብዝቶአል፤እንደ፡ዓቅማቸው፡መጠን፡
ከዓቅማቸውም፡የሚያልፍ፡እንኳ፡ወደው፡
፬፤ እንደ፡ሰጡ፡እመሰክርላቸዋለሁና ። ለቅዱሳን፡
በሆነው፡አገልግሎት፡እንዲተባበሩ፡ይህን፡
ቸርነት፡በብዙ፡ልመና፡ከእኛ፡ይለምኑ፡ነበር፥
፭፤ አስቀድመውም፡በእግዚአብሔር፡ፈቃድ፡ራስ
ቸውን፡ለጌታ፡ለእኛም፡ሰጡ፡እንጂ፡እንዳ
፮፤ ሰብን፡አይደለም ። ስለዚህም፡ቲቶ፡አስቀ
ድሞ፡እንደ፡ጀመረ፡እንዲሁ፡ደግሞ፡ይህን፡
ቸር፡ሥራ፡ደግሞ፡በእናንተ፡ዘንድ፡ሊፈ
፯፤ ጽም፡ለመንነ ። ነገር፡ግን፡በነገር፡ሁሉ፥በእ
ምነትና፡በቃል፡በእውቀትም፡በትጋትም፡
ሁሉ፡ለእኛም፡በፍቅራችሁ፡እንደ፡ተረፋ
ችሁ፥በዚህ፡ቸር፡ሥራ፡ደግሞ፡ትረፉ ።
፰፤ ትእዛዝ፡እንደምሰጥ፡አልልም፥ነገር፡ግን፡
በሌሎች፡ትጋት፡በኩል፡የፍቅራችሁን፡እው
፱፤ ነተኛነት፡ደግሞ፡ልመረምር፡እላለሁ፤የጌታ
ችንን፡የኢየሱስ፡ክርስቶስን፡ቸር፡በጐ፡
እውቃችኋልና፤ሀብታም፡ሲሆን፥እናንተ፡
በእርሱ፡ድህነት፡ባለ፡ጠጎች፡ትሆኑ፡ዘንድ፡
፲፤ ስለ፡እናንተ፡ድሀ፡ሆነ ። በዚህም፡ነገር፡ምክር፡
እሰጣለሁ፤ከአምና፡ጀምራችሁ፡ለማድረግ፡
ብቻ፡ያይደለ፡ነገር፡ግን፡ለማሰብ፡ደግሞ፡
አስቀድማችሁ፡የጀመራችሁት፡ይህ፡ይጠቅማ
፲፩፤ ችኋልና፤አሁንም፡ለማሰብ፡በጎ፡ፈቃድ፡
እንደ፡ነበረ፥እንዲሁ፡እንዳላችሁ፡መጠን፡
መፈጸም፡ደግሞ፡ይሆን፡ዘንድ፥ማድረጉን፡
፲፪፤ ደግሞ፡ፈጽሙ ። በጎ፡ፈቃድ፡ቢኖር፥እንዳ
ለው፡መጠን፡የተወደደ፡ይሆናል፡እንጂ፡እን
፲፫፤ ደሌለው፡መጠን፡አይደለም ። ለሌሎች፡ዕረ
ፍት፡ለእናንተም፡መከራ፡እንዲሆን፡አይደ
፲፬፤ ለም፥ትክክል፡እንዲሆን፡ነው፡እንጂ፤የእ
ነርሱ፡ትርፍ፡ደግሞ፡የእናንተን፡ጕድለት፡
እንዲሞላ፡በአሁኑ፡ጊዜ፡የእናንተ፡ትርፍ፡
የእነርሱን፡ጕድለት፡ይሞላ፤በትክክል፡እን
፲፭፤ ዲሆን፥እንዲህ፡ተብሎ፡እንደ፡ተጻፈ—ብዙ፡
ያከማቸ፡አላተረፈም፥ጥቂትም፡ያከማቸ፡አላ
ጐደለም ።
፲፮፤ ነገር፡ግን፡በቲቶ፡ልብ፡ስለ፡እናንተ፡ያንን፡
፲፯፤ ትጋት፡የሰጠ፡እግዚአብሔር፡ይመስገን፤ምክራች
ንን፡ተቀብሎአልና፥ትጋት፡ግን፡ስለ፡በዛ
፲፰፤ በት፡ወዶ፡ወደ፡እናንተ፡ይወጣል ። ከእ
ርሱም፡ጋር፡ስለ፡ወንጌል፡ሥራት፡በአብ
ያተ፡ክርስቲያናት፡ሁሉ፡የተመሰገነውን፡ወን
፲፱፤ ድም፡እንልካለን፤ይህም፡ብቻ፡አይደለም፡
ነገር፡ግን፡የጌታን፡የራሱን፡ክብርና፡የእኛን፡
በጎ፡ፈቃድ፡ለማስየት፡በምናገለግለው፡በዚህ፡
ቸር፡ሥራ፡ከእኛ፡ጋር፡እንዲጓደድ፡በአብ
፳፤ ያተ፡ክርስቲያናት፡ደግሞ፡ተመረጠ ። ስለም
ናገለግለው፡ስለዚህ፡ለጋስ፡ስጦታ፡ማንም፡
፳፩፤ እንዳይነቅፈን፡እንጠነቀቃለን፤በጌታ፡ፊት፡
ብቻ፡ያይደለ፡ነገር፡ግን፡በሰው፡ፊት፡ደግሞ፡
፳፪፤ መልካም፡የሆነውን፡እናስበለንና ። ብዙ፡
ጊዜም፡በብዙ፡ነገር፡መርምረን፡ትጉ፡እንደ፡
ሆነ፡ያገኘነውን፥አሁንም፡በእናንተ፡እጅግ፡
ስለሚታመን፡ከፊት፡ይልቅ፡እጅግ፡ትጉ፡
የሚሆነውን፡ወንድማችንን፡ከእነርሱ፡ጋር፡
፳፫፤ እንልካለን ። ስለ፡ቲቶ፡የሚጠይቅ፡ቢኖር፡
ስለ፡እናንተ፡አብሮኝ፡የሚሠራ፡ባልንጀራዬ፡
ነው፤ስለ፡ወንድሞቻችን፡የሚጠይቅ፡ቢኖ
ርም፡የአብያተ፡ክርስቲያናት፡መልእክተኞ
ችና፡የክርስቶስ፡ክብር፡ናቸው ። እንግዲህ፡ ፳፬፤

፯። ፰፤ ም. ፪፥፬። ፲፤ ማቴ. ፳፯፥፫፤፳፯፥፫—፭ ። ፲፭፤ ም. ፪፥፱ ።
፰። ፩—፬፤ ሮሜ ፲፭፥፳፭፡፳፯። ፯፤ ፩ ቆሮ. ፩፥፭፤፲፪፥፩፡፪። ፱፤ ማቴ. ፰፥፳፤ፊልጵ. ፪፥፯፡፰። ፲፤ ም. ፱፥
፪። ፲፪፤ ማር. ፲፪፥፵፫፡፵፬። ፲፭፤ ም. ፬፥፲፪። ፲፭፤ ዘፀአ. ፲፮፥፲፰። ፳፩፤ ሮሜ ፲፪፥፲፯።

የፍቅራችሁንና፡ ስለ፡ እናንተ፡ ያለውን፡ የት
ምክህታችንን፡ መግለጫ፡ በአብያተ፡ ክርስቲ
ያናት፡ ፊት፡ ለእነርሱ፡ ግለጡ ።

ምዕራፍ፡ ፱ ።

፩፤ ለቅዱሳን፡ ስለሚሆነው፡ አገልግሎት፡ ልጽ
፪፤ ፍላችሁ፡ አያስፈልግምና ፤ በጎ፡ ፈቃዳችሁን፡
አውቄአለሁና ፤ ስለዚህም፡— አካይያ፡ ከአምና፡
ጀምሮ፡ ተዘጋጅቶአል፡ ብዬ፡ ለመቄዶንያ፡
ሰዎች፡ በእናንተ፡ እመካለሁ ፤ ቅንዓታችሁም፡
፫፤ የሚበዙቱን፡ አነሣሥቶአል ። ነገር፡ ግን፡ ለእ
ነርሱ፡ እንዳልሁ፡ የተዘጋጃችሁ፡ ትሆኑ፡ ዘንድ፡
በዚህም፡ ነገር፡ ስለ፡ እናንተ፡ ያለው፡ ትምክ
ህታችን፡ ከንቱ፡ እንዳይሆን፡ ወንድሞችን፡
፬፤ እልካለሁ ፤ ምናልባት፡ የመቄዶንያ፡ ሰዎች፡
ከእኔ፡ ጋር፡ ቢመጡ፡ ያልተዘጋጃችሁም፡ ሆና
ችሁ፡ ቢያገኙአችሁ፡ እናንተ፡ እንድታፍሩ፡
አላልንም፡ እኛ፡ ግን፡ በዚህ፡ እምነታችን፡ እን
፭፤ ድናፍር፡ አይሁን ። እንግዲህ፡ እንደ፡ በረከት፡
ሆኖ፡ ከስስት፡ የማይሆን፡ ይህ፡ የተዘጋጀ፡
ይሆን፡ ዘንድ፡ አስቀድመው፡ ወደ፡ እናንተ፡
መጥተው፡ አስቀድማችሁ፡ ተስፋ፡ የሰጣችሁ
ትን፡ በረከት፡ አስቀድመው፡ እንዲፈጽሙ፡
ወንድሞችን፡ እለምን፡ ዘንድ፡ እንዲያስፈል
ገኝ፡ አሰብሁ ።
፮፤ ይህንም፡ እላለሁ፡— በጥቂት፡ የሚዘራ፡ በጥ
ቂት፡ ደግሞ፡ ያጭዳል፤ በበረከትም፡ የሚዘራ፡
፯፤ በበረከት፡ ደግሞ፡ ያጭዳል ። እግዚአብሔር፡
በደስታ፡ የሚሰጠውን፡ ይወዳልና፡ እያንዳንዱ፡
በልቡ፡ እንዳሰበ፡ ይስጥ፤ በኀዘን፡ ወይም፡
በግድ፡ አይደለም ።
፱፤ በተን፤ ለምስኪኖች፡ ሰጠ፤ ጽድቁ፡ ለዘላ
ለም፡ ይኖራል፡
ተብሎ፡ እንደ፡ ተጻፈ፤ እግዚአብሔር፤ ሁል
ጊዜ፡ በነገር፡ ሁሉ፡ ብቃትን፡ ሁሉ፡ አግኝታ
ችሁ፡ ለበጎ፡ ሥራ፡ ሁሉ፡ ትበዙ፡ ዘንድ፤ ጸጋን፡
፲፤ ሁሉ፡ ሊያበዛላችሁ፡ ይችላል ። ለዘሪ፡ ዘርን፡
ለመብላትም፡ እንጀራን፡ በብዙ፡ የሚሰጥ፡ እር
ሱም፡ የምትዘሩትን፡ ዘር፡ ይሰጣችኋል፡ ያበረ
ክትላችሁማል፤ የጽድቃችሁንም፡ ፍሬ፡ ያሳድ
፲፩፤ ጋል ፤ በእኛ፡ በኩል፡ ለእግዚአብሔር፡ የምስ
ጋና፡ ምክንያት፡ የሚሆነውን፡ ልግስና፡ ሁሉ፡
እንድታሳዩ፡ በሁሉ፡ ነገር፡ ባለ፡ ጠጎች፡ ትሆ
፲፪፤ ናላችሁ ። የዚህ፡ ረድኤት፡ አገልግሎት፡ ለቅ
ዱሳን፡ የሚጐድላቸውን፡ በሙሉ፡ የሚሰጥ፡
ብቻ፡ አይደለምና፤ ነገር፡ ግን፡ ደግሞ፡ በብዙ፡
፲፫፤ ምስጋና፡ ለእግዚአብሔር፡ ይበዛል ፤ በዚህ፡
አገልግሎት፡ ስለ፡ ተፈተናችሁ፤ በክርስቶስ፡
ወንጌል፡ በማመናችሁ፡ ስለሚሆን፡ መታዘዝ፡
እነርሱንና፡ ሁሉንም፡ ስለምትረዱበት፡ ልግ
፲፬፤ ስና፡ እግዚአብሔርን፡ ያከብራሉ፤ ራሳቸውም፡
ስለ፡ እናንተ፡ ሲያማልዱ፤ በእናንተ፡ ላይ፡ ከሚ
ሆነው፡ ከሚበልጠው፡ ከእግዚአብሔር፡ ጸጋ፡
፲፭፤ የተነሣ፡ ይናፍቁአችኋል ። ስለማይነገር፡ ስጦ
ታው፡ እግዚአብሔር፡ ይመስገን ።

ምዕራፍ፡ ፲ ።

፩፤ እኔም፡ ራሴ፡ ጳውሎስ፤ በእናንተ፡ ዘንድ፡
ፊት፡ ለፊት፡ ሳለሁ፡ ትሑት፡ የሆንሁ፤ ከእና
ንተ፡ ግን፡ ብርቅ፡ የምደፍራችሁ፤ በክርስቶስ፡
፪፤ የዋህነትና፡ ገርነት፡ እመክራችኋለሁ ፤ በዓለ
ማዊ፡ ልማድ፡ እንደምንመላለስ፡ በሚቈጥሩን፡
በአንዳንዶች፡ ላይ፡ እምኜ፡ ልደፍር፡ አስበ
ለሁ፤ በዚያ፡ እምነት፡ ግን፡ ከእናንተ፡ ጋር፡
፫፤ ሆኜ፡ እንዳልደፍር፡ እለምናችኋለሁ ። በሰው፡
ልማድ፡ ምንም፡ እንኳ፡ የምንመላለስ፡ ብን
፬፤ ሆን፤ እንደ፡ ሰው፡ ልማድ፡ አንዋጋም ፤ የጦር፡
ዕቃችን፡ ሥጋዊ፡ አይደለምና፤ ምሽግን፡ ለመ
ስበር፡ ግን፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ብርቱ፡ ነው ፤
፭፤ የሰውንም፡ አሳብ፡ በእግዚአብሔርም፡ እው
ቀት፡ ላይ፡ የሚነሣውን፡ ከፍ፡ ያለውን፡ ነገር፡
ሁሉ፡ እናፈርሳለን፡ ለክርስቶስም፡ ለመታዘዝ፡
፮፤ አእምሮን፡ ሁሉ፡ እንማርካለን፤ መታዘዛች
ሁም፡ በተፈጸመች፡ ጊዜ፡ አለመታዘዝን፡ ሁሉ፡
ልንበቀል፡ ተዘጋጅተናል ።
፯፤ በፊታችሁ፡ ያለውን፡ ተመልከቱ ። ማንም፡
የክርስቶስ፡ መሆኑን፡ ተረድቶ፡ ቢሆን፤ ይህን፡
እንደ፡ ገና፡ በራሱ፡ ይቍጠረው ፤ እርሱ፡ የክ
ርስቶስ፡ እንደ፡ ሆነ፡ እኛ፡ ደግሞ፡ እንዲሁ፡
፰፤ ነን ። ጌታ፡ እናንተን፡ ለማነጽ፡ እንጂ፡ እናን
ተን፡ ለማፍረስ፡ ያይደለ፡ በሰጠው፡ በሥልጣ
ናችን፡ ከፊት፡ ይልቅ፡ ብመካ፡ እንኳ፡ አላፍ
፱፤ ርም ። በመልእክቶቼ፡ የማስደነግጣችሁ፡ አይ
፲፤ ምስላችሁ ። መልእክቶቼስ፡ ከባድና፡ ኃይለኞ
ናቸው፤ ሰውነቱ፡ ግን፡ ሲታይ፡ ደካማ፡ ነው፤
፲፩፤ ንግግሩም፡ የተናቀ፡ ነው፡ ይላሉና ። እንዲሁ፡
የሚል፡ ይህን፡ ይቍጠረው ፤ በሩቅ፡ ሳለን፡ በመ
ልእክታችን፡ በኩል፡ በቃል፡ እንዳለን፤ በፊቱ፡
፲፪፤ ደግሞ፡ ሳለን፡ በሥራ፡ እንዲሁ፡ ነን ። ራሳቸ
ውን፡ ከሚያመሰግኑ፡ ከአንዳንዶች፡ ጋር፡ ራሳ
ችንን፡ ልንቈጥር፡ ወይም፡ ራሳችንን፡ ልናስ
ተያይ፡ አንደፍርምና ፤ ነገር፡ ግን፡ እነርሱ፡
ራሳቸውን፡ ከራሳቸው፡ ጋር፡ ሲያመዛዝኑ፤
ራሳቸውንም፡ ከራሳቸው፡ ጋር፡ ሲያስተያዩ፤
አያስተውሉም ።
፲፫፤ እኛ፡ ግን፡ እግዚአብሔር፡ እንደ፡ ወሰነልን፡
እስከ፡ እናንተ፡ እንኳ፡ እንደሚደርስ፡ እንደ፡
ክፍላችን፡ ልክ፡ እንጂ፡ ያለ፡ ልክ፡ አንመካም ።
፲፬፤ ወደ፡ እናንተ፡ እንደማንደርስ፡ አድርገን፡ ከመ
ጠን፡ አናልፍምና፤ የክርስቶስን፡ ወንጌል፡ በመ

፱። ፪፤ ምዕ· ፰፥፲። ፫፤ ምዕ· ፰፥፳፪። ፮፤ ምሳ· ፲፩፥፳፬። ፯፤ ዘዳ· ፲፭፥፲፤ ዘጸ· ፳፭፥፪። ፰፤ ፊልጵ· ፬፥፲፱። ፱፤ መዝ· ፻፲፩፥፱። ፲፤ ኢሳ· ፶፭፥፲፤ ሆሴ· ፲፥፲፪። ፲፬፤ ምዕ· ፰፥፲፬።
፲። ፩፤ ፩ ቆሮ· ፪፥፫። ፪፤ ፩ ቆሮ· ፬፥፳፩። ፬፤ ኤር· ፩፥፲፤ ኤፌ· ፮፥፲፫–፲፯። ፯፤ ዮሐ· ፯፥፳፬። ፲፯፤ ፩ ቆሮ· ፩፥፴፩። ፲፰፤ ምሳ· ፳፯፥፪።

ስበክ ፡ እስከ ፡ እናንተ ፡ እንኳ ፡ ደርሰናልና ፤
፲፭፣፲፮ በሌሎች ፡ ድካም ፡ ያለ ፡ ልክ ፡ አንመካም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እምነታችሁ ፡ ሲያድግ ፡ ከእናንተ ፡ ወዲያ ፡ ባለው ፡ አገር ፡ እስከንሰብክ ፡ ሥራችንን ፡ እየ ጨመርን ፤ በክፍላችን ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ እን ድንከብር ፡ ተስፋ ፡ እናደርጋለን ፤ በሌላው ፡ ክፍል ፡ ስለ ፡ ተዘጋጀው ፡ ነገር ፡ አንመካም ።
፲፯፣፲፰ የሚመካ ፡ ግን ፡ በጌታ ፡ ይመካ ፤ እግዚአብሔር ፡ የሚያመሰግነው ፡ እንጂ ፡ ራሱን ፡ የሚያመሰ ግን ፡ እርሱ ፡ ተፈትኖ ፡ የሚወጣ ፡ አይደለምና ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩ በጥቂቱ ፡ ሞኝነቴ ፡ ብትታገሡኝ ፡ መልካም ፡ ይሆን ፡ ነበር ፤ ቢሆንም ፡ በእርግጥ ፡ ታገሡኝ ።
፪ በእግዚአብሔር ፡ ቅንዓት ፡ እቀናላችኋለሁና ፤ እንደ ፡ ንጽሕት ፡ ድንግል ፡ እናንተን ፡ ለክርስ ቶስ ፡ ላቀርብ ፡ ለአንድ ፡ ወንድ ፡ አጭቻችኋለ
፫ ሁና ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እባብ ፡ በተንኰሉ ፡ ሔዋንን ፡ እንዳሳታት ፤ አሳባችሁ ፡ ተበላሽቶ ፡ ለክርስቶስ ፡ ከሚሆን ፡ ቅንነትና ፡ ንጽሕና ፡ ምናልባት ፡ እን
፬ ዳይለወጥ ፡ ብዬ ፡ እፈራለሁ ። የሚመጣውም ፡ ያልሰበክነውን ፡ ሌላ ፡ ኢየሱስ ፡ ቢሰብክ ፤ ወይም ፡ ያላገኛችሁትን ፡ ልዩ ፡ መንፈስ ፡ ወይም ፡ ያልተ ቀበላችሁትን ፡ ልዩ ፡ ወንጌል ፡ ብታገኙ ፤ በመል
፭ ካም ፡ ትታገሡታላችሁ ። ከእነዚህ ፡ ከዋናዎቹ ፡ ሐዋርያት ፡ በአንድ ፡ ነገር ፡ እንኳ ፡ እንደ ፡ ጐደ
፮ ልሁ ፡ ራሴን ፡ አልቈጥርም ። በአነጋገሬ ፡ ያል ተማርሁ ፡ ብሆን ፡ እንኳ ፤ በእውቀት ፡ ግን ፡ እን ዲሁ ፡ አይደለሁም ። ነገር ፡ ግን ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡ መካከል ፡ በነገር ፡ ሁሉ ፡ ተገልጠንላችኋል ።
፯ ወይስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ወንጌል ፡ ያለ ፡ ደመ ወዝ ፡ ስለ ፡ ሰበክሁላችሁ ፤ እናንተ ፡ ከፍ ፡ እን ድትሉ ፡ ራሴን ፡ እያዋረድሁ ፡ ኃጢአት ፡ አድ
፰ ርጌ ፡ ይሆንን ? እናንተን ፡ ለማገልገል ፡ ደመ ወዝ ፡ እየተቀበልሁ ፡ ሌሎችን ፡ አብያተ ፡ ክርስ
፱ ቲያናት ፡ ዘረፍሁ ። ከእናንተም ፡ ጋር ፡ ሳለሁ ፡ ስጐድለኝ ፡ ጊዜ ፤ በማንም ፡ አልከበድሁበትም ፤ ከመቄዶንያ ፡ የመጡት ፡ ወንድሞች ፡ የጐደለ ኝን ፡ በሙሉ ፡ ሰጥተዋልና ፤ በነገርም ፡ ሁሉ ፡ እንዳልከብድባችሁ ፡ ተጠንቀቅሁ ፡ እጠነቀቅማ
፲ ለሁ ። የክርስቶስ ፡ እውነት ፡ በእኔ ፡ እንዳለ ፤ ይህ ፡ ትምክህት ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ በአካይያ ፡ አገር ፡
፲፩ አይከለከልም ። ስለ ፡ ምን ? ስለማልወዳችሁ ፡ ነውን ? እግዚአብሔር ፡ ያውቃል ።
፲፪ ነገር ፡ ግን ፡ በዚያ ፡ በሚመኩበት ፡ እንደ ፡ እኛ ፡ ሆነው ፡ ሊገኙ ፤ ምክንያትን ፡ ከሚፈል ጉቱ ፡ ምክንያትን ፡ እቈርጥ ፡ ዘንድ ፡ አሁን ፡ የማ ደርገውን ፡ ከዚህ ፡ ወዲህ ፡ ደግሞ ፡ አደርጋለሁ ።
፲፫ እንደ ፡ እነዚህ ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ የክርስቶስን ፡ ሐዋ ርያት ፡ እንዲመስሉ ፡ ራሳቸውን ፡ እየለወጡ ፤ ውሸተኞች ፡ ሐዋርያትና ፡ ተንኰለኞች ፡ ሠራ
፲፬ ተኞች ፡ ናቸውና ። ይህም ፡ ድንቅ ፡ አይደለም ፤ ሰይጣን ፡ ራሱ ፡ የብርሃንን ፡ መልአክ ፡ እንዲመ
፲፭ ስል ፡ ራሱን ፡ ይለውጣልና ። እንግዲህ ፡ አገል ጋዮቹ ፡ ደግሞ ፡ የጽድቅን ፡ አገልጋዮች ፡ እን ዲመስሉ ፡ ራሳቸውን ፡ ቢለውጡ ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡ አይደለም ፤ ፍጻሜአቸውም ፡ እንደ ፡ ሥራቸው ፡ ይሆናል ።
፲፮ እንደ ፡ ገና ፡ እላለሁ ፦ ለማንም ፡ ሰው ፡ ሞኝ ፡ የሆንሁ ፡ አይምሰለው ፤ ያለዚያ ፡ ግን ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ ጥቂት ፡ እመካ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ሞኝ ፡
፲፯ እንኳ ፡ ሆኜ ፡ ተቀበሉኝ ። እንደዚህ ፡ ታምኜ ፡ ስመካ ፡ የምናገረው ፤ በሞኝነት ፡ እንጂ ፡ ጌታ ፡
፲፰ እንዳዘዘኝ ፡ አልናገርም ። ብዙዎች ፡ በዓለማዊ ፡ ነገር ፡ ስለሚመኩ ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ እመካለሁ ።
፲፱ ልባሞች ፡ ስለምትሆኑ ፡ በደስታ ፡ ሞኞችን ፡
፳ ትታገሣላችሁና ፤ ማንም ፡ ባሪያዎች ፡ ቢያደርጋ ችሁ ፤ ማንም ፡ ቢበላችሁ ፤ ማንም ፡ ቢቀማችሁ ፤ ማንም ፡ ቢኰራባችሁ ፤ ማንም ፡ ፊታችሁን ፡
፳፩ በጥፊ ፡ ቢመታችሁ ፡ ትታገሣላችሁና ። ደካ ሞች ፡ መስለን ፡ እንደ ፡ ነበርን ፡ በውርደት ፡ እላ ለሁ ።

ነገር ፡ ግን ፡ በሞኝነት ፡ እላለሁ ፤ ማንም ፡ በሚ ደፍርበት ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ እደፍርበታለሁ ።
፳፪ ዕብ ራውያን ፡ ናቸውን ? እኔ ፡ ደግሞ ፡ ነኝ ። የእስ ራኤል ፡ ወገን ፡ ናቸውን ? እኔ ፡ ደግሞ ፡ ነኝ ። የአብርሃም ፡ ዘር ፡ ናቸውን ? እኔ ፡ ደግሞ ፡ ነኝ ።
፳፫ የክርስቶስ ፡ አገልጋዮች ፡ ናቸውን ? እንደ ፡ እብድ ፡ ሰው ፡ እላለሁ ፤ እኔ ፡ እበልጣለሁ ፤ በድ ካም ፡ አብዝቼ ፤ በመገረፍ ፡ አብዝቼ ፤ በመታ ሰር ፡ አትርፌ ፤ በመሞት ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ሆንሁ ።
፳፬ አይሁድ ፡ አንድ ፡ ሲጐድል ፡ አርባ ፡ ግርፋት ፡
፳፭ አምስት ፡ ጊዜ ፡ ገረፉኝ ። ሦስት ፡ ጊዜ ፡ በበ ትር ፡ ተመታሁ ፤ አንድ ፡ ጊዜ ፡ በድንጋይ ፡ ተወ ገርሁ ፤ መርከቡ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ተሰበረ ፤ ሌሊ ትና ፡ ቀን ፡ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ ኖርሁ ።
፳፮ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ በመንገድ ፡ ሄድሁ ፤ በወንዝ ፡ ፍርሃት ፤ በወንበዴዎች ፡ ፍርሃት ፤ በወገኔ ፡ በኩል ፡ ፍር ሃት ፤ በአሕዛብ ፡ በኩል ፡ ፍርሃት ፤ በከተማ ፡ ፍርሃት ፤ በምድረ ፡ በዳ ፡ ፍርሃት ፤ በባሕር ፡ ፍርሃት ፤ በውሸተኞች ፡ ወንድሞች ፡ በኩል ፡ ፍርሃት ፡ ነበረብኝ ፤
፳፯ በድካምና ፡ በጥረት ፡ ብዙ ፡ ጊዜም ፡ እንቅልፍ ፡ በማጣት ፤ በራብና ፡ በጥም ፡ ብዙ ፡ ጊዜም ፡ በመጦም ፤ በብርድና ፡ በራቁት ነት ፡ ነበርሁ ።
፳፰ የተረፈውንም ፡ ነገር ፡ ሳልቈጥር ፤ ዕለት ፡ ዕለት ፡ የሚከብድብኝ ፡ የአብያተ ፡ ክርስ
፳፱ ቲያናት ፡ ሁሉ ፡ አሳብ ፡ ነው ። የሚደክም ፡ ማን ፡ ነው ፤ እኔም ፡ አልደክምምን ? የሚሰናከል ፡

፲ ። ፲፭ ፤ ሮሜ ፲፭ ፥ ፳ ። ፲፯ ፤ ፩ ቆሮ ፩ ፥ ፴፩ ። ፲፰ ፤ ፩ ቆሮ ፬ ፥ ፭ ።
፲፩ ። ፪ ፤ ሆሴ ፪ ፥ ፲፱ ፤ ኤፌ ፭ ፥ ፳፮ ፤ ፳፯ ። ፫ ፤ ዘፍጥ ፫ ፥ ፬ ። ፬ ፤ ገላ ፩ ፥ ፯ ፤ ፰ ። ፭ ፤ ገላ ፪ ፥ ፮ ። ፮ ፤ ፩ ቆሮ ፪ ፥ ፩ ፤ ፬ ፤ ፲፫ ። ፯ ፤ የሐዋ ፲፰ ፥ ፫ ። ፱ ፤ ፩ ቆሮ ፲፮ ፥ ፲፯ ። ፲ ፤ ፩ ቆሮ ፱ ፥ ፲፭ ። ፲፪ ፤ ፩ ቆሮ ፱ ፥ ፲፪ ። ፲፫ ፤ ማቴ ፯ ፥ ፲፭ ። ፳፪ ፤ ፊልጵ ፫ ፥ ፭ ። ፳፫ ፤ ፩ ቆሮ ፲፭ ፥ ፲ ። ፳፬ ፤ የሐዋ ፲፬ ፥ ፲፱ ። ፳፭ ፤ የሐዋ ፲፮ ፥ ፳፪ ። ፳፮ ፤ ፩ ቆሮ ፬ ፥ ፲፩ ። ፳፱ ፤ ፩ ቆሮ ፱ ፥ ፳፪ ።

ማን፡ነው፥ እኔም፡አልናደድምን ?

፴ ትምክህት፡የሚያስፈልግ፡ከሆነ፥ከድካሜ፡ በሚሆነው፡ነገር፡እመካለሁ ። ፴፩ ለዘላለም፡የተባረከ፡የጌታችን፡የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡አምላክና፡አብት፡እንዳልዋሽ፡ያውቃል ። ፴፪ በደማስቆ፡አርስጦስዮስ፡ከተበስ፡ንጉሥ፡በታች፡የሆነ፡የሕዝብ፡ገዥ፡ሊይዘኝ፡እየወደደ፡የደማስቆ፡ሰዎችን፡ከተማ፡ያስጠብቅ፡ነበር፥ ፴፫ በቅጥሩም፡በላ፡መስኮት፡በቅርጫት፡አወረዱኝና፡ከእጁ፡አመለጥሁ ።

## ምዕራፍ፡ ፲፪ ።

፩ ትምክህት፡የሚያስፈልግ፡ነው ፤ አይጠቅምም፡ነገር፡ግን፡ከጌታ፡ወደለው፡ራእይና፡ ፪ መገለጥ፡እመጣለሁ ። ሰውን፡በክርስቶስ፡አውቃለሁ፥በሥጋ፡እንደ፡ሆነ፡አላውቅም፡ወይም፡ከሥጋ፡ውጭ፡እንደ፡ሆነ፡አላውቅም፥እግዚአብሔር፡ያውቃል ፤ እንዲህ፡ያለው፡ሰው፡ከአሥራ፡አራት፡ዓመት፡በፊት፡እስከ፡ ፫ ሦስተኛው፡ሰማይ፡ድረስ፡ተነጠቀ ። እንዲህ፡ያለውንም፡ሰው፡አውቃለሁ፥በሥጋ፡እንደ፡ሆነ፡ወይም፡ያለ፡ሥጋ፡እንደ፡ሆነ፡አላው ፬ ቅም፥እግዚአብሔር፡ያውቃል ፤ ወደ፡ገነት፡ተነጠቀ፥ሰውም፡ሊናገር፡የማይገባውን፡የማ ፭ ይነገረውን፡ቃል፡ሰማ ። እንደዚህ፡ስላለው፡እመካለሁ ፥ ስለ፡ራሴ፡ግን፡ከድካሜ፡በቀር፡ ፮ አልመካም ። ልመካ፡ብወድስ፡ሞኝ፡አልሆንም ፥ እውነትን፡እላለሁና ፤ ነገር፡ግን፡ማንም፡ከሚያይ፡ከእኔም፡ከሚሰማ፡የምበ ፯ ልጥ፡አድርጎ፡እንዳይቈጥረኝ፡ትቼአለሁ ። ስለዚህም፡በመገለጥ፡ታላቅነት፡እንዳልታበይ፡የሥጋዬ፡መውጊያ ፥ እርሱም፡የሚጐስመኝ፡የሰይጣን፡መልእክተኛ፡ተሰጠኝ ፤ ይኸውም፡ ፰ እንዳልታበይ፡ነው ። ስለዚህ፡ነገር፡ከእኔ፡ ፱ እንዲለይ፡ሦስት፡ጊዜ፡ጌታን፡ለመንሁ ። እርሱም፦ ጸጋዬ፡ይበቃሃል፥ኃይሌ፡በድካም፡ይፈጸማልና፡አለኝ ። እንግዲህ፡የክርስቶስ፡ኃይል፡ያድርብኝ፡ዘንድ፡በብዙ፡ደስታ፡በድ ፲ ካሜ፡ልመካ፡እወዳለሁ ። ስለዚህ፡ስለ፡ክርስቶስ፡በድካም፡በመንገላታትም፡በችግርም፡በስደትም፡በጭንቀትም፡ደስ፡ይለኛል ፤ ስደክም፡ያን፡ጊዜ፡ኃይለኛ፡ነኝና ።

፲፩ በመመካቴ፡ሞኝ፡ሆኜአለሁ ፤ እናንተ፡ግድ፡አላችሁኝ ፤ እናንተ፡እኔን፡ልታመሰግኑ፡ይገባ፡ነበርና ። እኔ፡ምንም፡ባልሆን፡እንኳ፥ከዋናዎቹ፡ሐዋርያት፡በምንም፡አልጐ ፲፪ ድልምና ። በእርግጥ፡የሐዋርያነት፡ምልክት፡በመካከላችሁ፡በምልክትና፡በድንቅ፡ነገር፡በተአምራትም፡በሁሉ፡ትዕግሥት፡ተደረገ ።

፲፫ እኔ፡ራሴ፡ካልከበድሁባችሁ፡ከዚህ፡በቀር፥ከሌላ፡ቤተ፡ክርስቲያን፡ያነሳችሁበት፡በምን፡እክ፡ነው ? ይህን፡በደሌን፡ይቅር፡በሉልኝ ።

፲፬ እነሆ፥ ወደ፡እናንተ፡እመጣ፡ዘንድ፡ስዘጋጅ፡ይህ፡ሦስተኛዬ፡ነው ፤ አልከብድባችሁምም፥እናንተን፡እንጂ፡ያላችሁን፡አልፈልግምና ። ወላጆች፡ስልጆች፡እንጂ፡ልጆች፡ስወላጆች፡ገንዘብ፡ሊያከማቹ፡አይገባቸውምና ። ፲፭ እኔ፡ግን፡ስለ፡ነፍሳችሁ፡በብዙ፡ደስታ፡ገንዘቤን፡እከፍላለሁ፥ራሴን፡እንኳ፡እከፍላለሁ ። ከመጠን፡ይልቅ፡ብወዳችሁ፡በዚህ፡ልክ፡ፍቅ ራችሁ፡የሚያንስ፡ነውን ? ፲፮ ይሁን፡እንጂ፡እኔ፡አልከበድሁባችሁም ፤ ነገር፡ግን፡ሸንጋይ፡ሆኜ፡በተንኰል፡ያዝኋችሁ ። ፲፯ ወደ፡እናንተ፡ከላክኋቸው፡በአንዱ፡ስንኳ፡አታለልኋችሁን ? ፲፰ ቲቶን፡መከርሁት፡ከእርሱም፡ጋር፡ወንድሙን፡ላክሁት ፤ ቲቶስ፡አታለላችሁን ? በአንድ፡መንፈስ፡አልተመላለስንምን ? በአንድ፡ፍለጋስ፡አልተመላለስንም ?

፲፱ ለእናንተ፡ስለ፡ራሳችን፡እንድንመልስ፡ሁልጊዜ፡ይመስላችኋልን ? በእግዚአብሔር፡ፊት፡በክርስቶስ፡ሆነን፡እንናገራለን ፤ ነገር፡ግን፥ወዳጆች፥እናንተን፡ልናንጻችሁ፡ሁሉን፡እንናገራለን ። ፳ ስመጣ፥ እንደምወደው፡ሳትሆኑ፡አገኛችሁ፡ይሆናል፡እኔም፡እንደምትወዱት፡ሳልሆን፡ታገኙኝ፡ይሆናል፡ብዬ፡እፈራለሁ ፤ ምናልባት፡ክርክር፡ቅንዓትም፡ቍጣም፡አድመኛነትም፡ሐሜትም፡ማሾክሾክም፡ኵራትም፡ሁከትም፡ይሆናሉ ፤ ፳፩ እንደ፡ገና፡ስመጣ፡በእናንተ፡ዘንድ፡አምላኬ፡እንዲያዋርደኝ፥አስቀድመውም፡ኃጢአት፡ከሠሩትና፡ስላደረጉት፡ርኵሰትና፡ዝሙት፡መዳራትም፡ንስሐ፡ካልገቡት፡ወገን፡ስለ፡ብዙዎች፡ምናልባት፡እዝናለሁ፡ብዬ፡እፈራለሁ ።

## ምዕራፍ፡ ፲፫ ።

፩ ወደ፡እናንተ፡ስመጣ፡ይህ፡ሦስተኛዬ፡ነው ፤ ሁሉ፡ነገር፡በሁለትና፡በሦስት፡ምስክር፡አፍ፡ ፪ ይጸናል ። ሁለተኛ፡በእናንተ፡ዘንድ፡በነበርሁ፡ጊዜ፡እንደ፡ተናገርሁ፡አሁንም፡ደግሞ፡በሩቅ፡ስሆን፥ክርስቶስ፡በእኔ፡አድሮ፡እንዲናገር፡ማስረጃ፡ከፈለጋችሁ፥እንደ፡ገና፡ብመጣ፡እንዳልራራላቸው፡አስቀድመው፡ኃጢአት፡ላደረጉት፡ለሌሎችም፡ሁሉ፡አስቀድሜ፡ብዬ፡አለሁ፥አስቀድሜም፡እላለሁ ። ክርስቶስም፡ስለ፡እናንተ፡አይደክምም፡ነገር፡ግን፡በእ ፬ ናንተ፡ኃይለኛ፡ነው ። በድካም፡ተሰቅሎአልና፥ነገር፡ግን፡በእግዚአብሔር፡ኃይል፡በሕይወት፡ይኖራል ። እኛ፡ደግሞ፡ከእርሱ፡ጋር፡

፲፩ ። ፴፪፡፴፫ ፤ የሐዋ. ፱፥ ፳፬፡፳፭ ።
፲፪ ። ፭ ፤ ምዕ. ፲፩፥፴ ። ፮ ፤ ሉቃ. ፲፫፥፲፯ ። ፯ ፤ ማቴ. ፭፥፲፩፡፲፪ ፤ ሮሜ ፩፥፫ ። ፲፩ ፤ ምዕ. ፲፩፥፭ ። ፲፪ ፤ ሮሜ ፲፭፥፲፱ ። ፲፫ ፤ ምዕ. ፲፩፥፱ ። ፲፬ ፤ ፩ ቆሮ. ፬፥፲፬ ። ፲፰ ፤ ምዕ. ፰፥፮፡፲፮፡፲፰ ። ፳ ፤ ፩ ቆሮ. ፩፥፲፩ ፤ ፫፥፫ ፤ ፬፥፮ ። ፳፩ ፤ ፩ ቆሮ. ፩፥፲ ።
፲፫ ። ፩ ፤ ዘዳግ. ፲፱፥፲፭ ። ፫ ፤ ፩ ቆሮ. ፭፥፬ ። ፬ ፤ ፊልጵ. ፪፥፯ ፤ […]

እንደክማለንና፤ነገር፡ግን፡ስለ፡እናንተ፡በሆነ፡ በእግዚአብሔር፡ኃይል፡ከእርሱ፡ጋር፡በሕይ ወት፡እንኖራለን ።

፭፤ በሃይማኖት፡ብትኖሩ፡ራሳችሁን፡መርምሩ ፤ ራሳችሁን፡ፈትኑ ፤ ወይስ፡ምናልባት፡የማት በቁ፡ብትሆኑ፤ኢየሱስ፡ክርስቶስ፡በእናንተ፡ ውስጥ፡እንዳለ፡ስለ፡እናንተ፡አታውቁምን ?

፮፤ እኛ፡ግን፡የማንበቃ፡እንዳይደለን፡ልታውቁ፡

፯፤ ተስፋ፡አደርጋለሁ ። ክፉ፡ነገርንም፡ከቶ፡ እንዳታደርጉ፡ወደ፡እግዚአብሔር፡እንጸልያ ለን ፤ እኛ፡የምንበቃ፡ሆነን፡እንገለጥ፡ዘንድ፡ አይደለም፡ነገር፡ግን፡እኛ፡ምንም፡እንደማ ንበቃ፡ብንሆን፤እናንተ፡መልካሙን፡ታደ

፰፤ ርጉ፡ዘንድ፡ነው ። ለእውነት፡እንጂ፡በእው ነት፡ላይ፡ምንም፡ለማድረግ፡አንችልምና ።

፱፤ እኛ፡ስንደክም፡እናንተም፡ኃይለኞች፡ስት ሆኑ፡ደስ፡ብሎናልና ፤ እናንተ፡ፍጹማን፡ ትሆኑ፡ዘንድ፡ለዚህ፡ደግሞ፡እንጸልያለን ።

፲፤ ስለዚህ፡ጌታ፡ለማፍረስ፡ያይደለ፡ለማነጽ፡ እንደ፡ሰጠኝ፡ሥልጣን፤ከእናንተ፡ጋር፡ሳለሁ፡ በቍርጥ፡እንዳልሠራ፡በሩቅ፡ሆኜ፡ይህን፡ እጽፋለሁ ።

፲፩፤ በቀረውስ፤ወንድሞች፡ሆይ፤ደኅና፡ሁኑ። ፍጹማን፡ሁኑ፤ምክሬን፡ስሙ፤በአንድ፡ልብ፡ ሁኑ፤በሰላም፡ኑሩ፤የፍቅርና፡የሰላምም፡አም ላክ፡ከእናንተ፡ጋር፡ይሆናል ።

፲፪፤ በተቀደሰ፡ አሳሳም፡እርስ፡በርሳችሁ፡ሰላምታ፡ተሰጣጡ ።

፲፫፤ ቅዱሳን፡ሁሉ፡ሰላምታ፡ያቀርቡላችኋል ።

፲፬፤ የጌታ፡የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ጸጋ፡የእግዚ አብሔርም፡ፍቅር፡የመንፈስ፡ቅዱስም፡ኅብ ረት፡ከሁላችሁ፡ጋር፡ይሁን ። አሜን ።

# የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ገላትያ ፡ ሰዎች ።

## ምዕራፍ፡፩ ።

ቁ፩፤ በኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ከሙታንም፡ባነሣው፡ በእግዚአብሔር፡አብ፡ሐዋርያ፡የሆነ፡እንጂ፡ ከሰዎች፡ወይም፡በሰው፡ያልሆነ፡ጳውሎስ፡ ከእኔም፡ጋር፡ያሉት፡ወንድሞች፡ሁሉ፤ወደ፡ ገላትያ፡አብያተ፡ክርስቲያናት ፤

፪፤ ከእግዚአብሔር፡ከአባታችን፡ከጌታችንም፡ ከኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ጸጋና፡ሰላም፡ለእናንተ፡

፫፤ ይሁን ። ክፉ፡ከሆነ፡ከአሁኑ፡ዓለም፡ያድነን፡ ዘንድ፡እንደ፡አምላካችንና፡እንደ፡አባታችን፡ ፈቃድ፡ስለ፡ኃጢአታችን፡ራሱን፡ሰጠ ።

፬፤ ለእርሱ፡ከዘላለም፡እስከ፡ዘላለም፡ክብር፡ይሁን ፤ አሜን ።

፭፤ በክርስቶስ፡ጸጋ፡እናንተን፡ከጠራችሁ፡ከእ ርሱ፡ወደ፡ልዩ፡ወንጌል፡እንዲህ፡ፈጥናችሁ፡

፮፤ እንዴት፡እንዳለፋችሁ፡እደነቃለሁ ፤ እርሱ፡ ግን፡ሌላ፡ወንጌል፡አይደለም ፤ የሚያናውጡ አችሁ፡የክርስቶስንም፡ወንጌል፡ሊያጣምሙ፡

፯፤ የሚወዱ፡አንዳንዶች፡አሉ፡እንጂ ። ነገር፡ ግን፡እኛ፡ብንሆን፡ወይም፡ከሰማይ፡መል አክ፤ከሰበክንላችሁ፡ወንጌል፡የሚለይ፡ወን

፰፤ ጌልን፡ቢሰብክላችሁ፤የተረገመ፡ይሁን ። አስ ቀድመን፡እንዳልን፡እንዲሁ፡አሁን፡ሁለተኛ፡ እላለሁ፤ከተቀበላችሁት፡የተለየውን፡ማንም፡ ቢሰብክላችሁ፡የተረገመ፡ይሁን ።

፱፤ ሰውን፡ወይስ፡እግዚአብሔርን፡አሁን፡እሺ፡ አሰኛለሁን ? ወይም፡ሰውን፡ደስ፡ላሰኝ፡እፈ ልጋለሁን ? አሁን፡ሰውን፡ደስ፡ባሰኝ፡የክር ስቶስ፡ባሪያ፡ባልሆንሁም ።

፲፩፤ ወንድሞች፡ሆይ፤በእኔ፡የተሰበከ፡ወን ጌል፡እንደ፡ሰው፡እንዳይደለ፡አስታውቃችኋ

፲፪፤ ለሁ ፤ ኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ገለጠልኝ፡እንጂ፡ እኔ፡ከሰው፡አልተቀበልሁትም፡አልተማርሁት

፲፫፤ ምም ። በአይሁድ፡ሥርዓት፡በፊት፡እንዴት፡ እንደ፡ኖርሁ፡ሰምታችኋልና ፤ የእግዚአብሔ ርን፡ቤተ፡ክርስቲያን፡ያለ፡ልክ፡አሳድድና፡

፲፬፤ አጠፋ፡ነበር፤ለአባቶችም፡ወግ፡ከመጠን፡ ይልቅ፡እየቀናሁ፡በወገኔ፡ዘንድ፡በዘመኔ፡ ካሉት፡ብዙዎችን፡በአይሁድ፡ሥርዓት፡እበ

፲፭፡፲፮፤ ልጥ፡ነበር ። ነገር፡ግን፡በእናቴ፡ማኅፀን፡ ሳለሁ፡የለየኝ፡በጸጋውም፡የጠራኝ፡እግዚአ ብሔር፡በአሕዛብ፡መካከል፡ስለ፡እርሱ፡ወን ጌልን፡እሰብክ፡ዘንድ፡ልጁን፡በእኔ፡ሊገልጥ፡ በወደደ፡ጊዜ፤ወዲያው፡ከሥጋና፡

፲፯፤ ከደም፡ጋር፡አልተማከርሁም፤ከእኔም፡በፊት፡ ሐዋርያት፡ወደ፡ነበሩት፡ወደ፡ኢየሩሳሌም፡ አልወጣሁም፤ነገር፡ግን፡ወደ፡ዓረብ፡አገር፡ ሄድሁ፡እንደ፡ገናም፡ወደ፡ደማስቆ፡ተመለ ስሁ ።

፲፰፤ ከዚህ፡ወዲያ፡ከሦስት፡ዓመት፡በኋላ፡ ኬፋን፡ልጠይቅ፡ወደ፡ኢየሩሳሌም፡ወጣሁ፡

፲፫። ፭፤ ገላ. ፮፡፫፡፬። ፱፤ ቆላ. ፩፡፳፰። ፲፤ ም. ፲፡፰። ፲፩፤ ሮሜ ፲፭፡፴፫። ፲፪፤ ፩ ቆሮ. ፲፮፡፳።

፩። ፪፤ የሐዋ. ፲፮፡፮። ፫፤ ፩ ቆሮ. ፩፡፫። ፬፤ ማቴ. ፳፡፳፰፤ ፩ ዮሐ. ፩፡፲፱። ፮፤ የሐዋ. ፲፮፡፩፡፳፱። ፲፤ ፩ ተሰ. ፪፡፬። ፲፪፤ ፩ ቆሮ. ፲፭፡፳፫። ፲፫፡፲፱፤ የሐዋ. ፰፡፫፤ ፳፫፡፫፤ ፱፤ ፳፮፡፩፡፲፡፲፩። ፲፭፤ ኤር. ፩፡፭። ፲፰፤ የሐዋ. ፱፡፳፯።

ከእርሱ፡ ጋር፡ አሥራ፡ አምስት፡ ቀን፡ ሰነበ ትሁ ፤ ፲፱ ነገር፡ ግን፡ ከጌታ፡ ወንድም፡ ከያዕቆብ፡ በቀር፡ ከሐዋርያት፡ ሌላ፡ አላየሁም ። ፳ ስለም ጽፍላችሁም፡ ነገር÷ እነሆ÷ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ሐሰት፡ አልናገርም ። ፳፩ ከዚያ፡ ወዲያ፡ ወደ፡ ሶርያና፡ ወደ፡ ኪልቅያ፡ አገር፡ መጣሁ ። ፳፪ በክ ርስቶስም፡ ያሉት፡ የይሁዳ፡ ማኅበሮች፡ ፊቱን፡ አያውቁም፡ ነበር ፤ ፳፫ ነገር፡ ግን፡—ቀድሞ፡ እኛን፡ ያሳድድ፡ የነበረ÷ እርሱ፡ በፊት፡ ያጠፋው፡ የነ በረውን፡ ሃይማኖት፡ አሁን፡ ይሰብካል፡ ተብሎ፡ ሲነገር፡ ይሰሙ፡ ነበር ፤ ፳፬ ስለ፡ እኔም፡ እግዚአ ብሔርን፡ ያከብሩ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ፡ ፪ ።

፩ ከዚያ፡ ወዲያ፡ ከአሥራ፡ አራት፡ ዓመት፡ በኋላ፡ ከበርናባስ፡ ጋር፡ ቲቶን፡ ደግሞ፡ ይዤ፡ ፪ ወደ፡ ኢየሩሳሌም፡ ሁለተኛ፡ ወጣሁ ፤ እንደ፡ ተገለጠልኝም፡ ወጣሁ ፤ ምናልባትም፡ በከንቱ፡ እንዳልሮጥ፡ ወይም፡ በከንቱ፡ ሮጬ፡ እንዳል ሆን፡ በአሕዛብ፡ መካከል፡ የምሰብከውን፡ ወን ጌል፡ አስታወቅኋቸው ፤ ዋኖች፡ ግን፡ መስለው፡ ፫ ለሚታዩ፡ ለብቻቸው፡ አስታወቅኋቸው ። ነገር፡ ግን፡ ከእኔ፡ ጋር፡ የነበረ፡ ቲቶ፡ እንኳ፡ የግሪክ፡ ሰው፡ሲሆን፡ ይገረዝ፡ ዘንድ፡ ግድ፡ አላሉትም ፤ ፬ ነገር፡ ግን፡ ባሪያዎች፡ ሊያደርጉን፡ በክርስቶስ፡ ኢየሱስ፡ ያለንን፡ አርነታችንን፡ ይሰልሉ፡ ዘንድ፡ ሾልከው፡ በስውር፡ ስለ፡ ገቡ፡ ስለ፡ ፭ ሐሰተኞች፡ ወንድሞች፡ ነበረ ። የወንጌልም፡ እውነት፡ በእናንተ፡ ዘንድ፡ ጸንቶ፡ እንዲኖር፡ ለአንድ፡ ሰዓት፡ እንኳ፡ ስቀቀን፡ አልተገዛንላ ፮ ቸውም ። አለቆች፡ የመሰሉት፡ ግን÷ በፊት፡ ማን፡ እንደ፡ ነበሩ፡ አይገደኝም ፤ እግዚአብ ሔር፡ የሰውን፡ ፊት፡ አይቶ፡ አያደላም ፤ አለ ቆች፡ የመሰሉት፡ አንዳች፡ እንኳ፡ አልጨመ ፯ ሩልኝምና÷ ተመልሰው፡ ግን፡ ጴጥሮስ፡ ለተ ገረዙት፡ የሆነው፡ ወንጌል፡ አደራ፡ እንደ፡ ተሰጠው፡ እንዲሁ፡ ለእኔ፡ ላልተገረዙት፡ የሆ ነው፡ ወንጌል፡ አደራ፡ እንደ፡ ተሰጠኝ፡ አዩ ፤ ፰ ለተገረዙት፡ ሐዋርያ፡ እንዲሆን፡ ለጴጥሮስ፡ የሠራለት÷ ለእኔ፡ ደግሞ፡ ለአሕዛብ፡ ሐዋርያ፡ ፱ እንድሆን፡ ሠርቶአልና ። ደግሞ፡ የተሰጠኝን፡ ጸጋ፡ አውቀው÷ አዕማድ፡ መስለው፡ የሚታዩ፡ ያዕቆብና፡ ኬፋ፡ ዮሐንስም፡ እኛ፡ ወደ፡ አሕዛብ፡ እነርሱም፡ ወደ፡ ተገረዙት፡ ይሄዱ፡ ዘንድ፡ ለእኔና፡ ለበርናባስ፡ ቀኝ፡ እጃቸውን፡ ሰጡን ፤ ፲ ድሆችን፡ እናስብ፡ ዘንድ፡ ብቻ፡ ለመኑን÷ ይህ ንም፡ ደግሞ፡ ላደርግ፡ ተጋሁ ።

፲፩ ነገር፡ ግን፡ ኬፋ፡ ወደ፡ አንጾኪያ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ፊት፡ ለፊት፡ ተቃወምሁት÷ ይፈረድበት፡ ዘንድ፡ ይገባ፡ ነበርና ። ፲፪ አንዳንድ፡ ከያዕቆብ፡ ዘንድ፡ ሳይመጡ፡ ከአሕዛብ፡ ጋር፡ አብሮ፡ ይበላ፡ ነበርና ፤ በመጡ፡ ጊዜ፡ ግን፡ ከተገረዙት፡ ወገን፡ ያሉትን፡ ፈርቶ፡ ያፈገፍግ፡ ነበርና፡ ከእ ነርሱ፡ ተለየ ። ፲፫ የቀሩትም፡ አይሁድ፡ ደግሞ÷ በርናባስ፡ስንኳ፡ በግብዝነታቸው፡ እስኪ፡ ተሳበ፡ ድረስ÷ ከእርሱ፡ ጋር፡ አብረው፡ ግብዞች፡ሆኑ ። ፲፬ ነገር፡ ግን፡ እንደ፡ ወንጌል፡ እውነት፡ በቅን ነት፡ እንዳልሄዱ፡ ባየሁ፡ ጊዜ፡ በሁሉ፡ ፊት፡ ኬፋን፡—አንተ፡ አይሁዳዊ፡ ሳለህ፡ በአይሁድ፡ ኑሮ፡ ያይደለ፡ በአሕዛብ፡ ኑሮ፡ ብትኖር÷ አሕ ዛብ፡ በአይሁድ፡ ኑሮ፡ ሊኖሩ፡ እንዴት፡ ግድ፡ አልሃቸው ? አልሁት ። ፲፭ እኛ፡ በፍጥረት፡ አይ ሁድ፡ነን፡ ኃጢአተኞችም፡ የሆኑ፡ አሕዛብ፡ አይ ደለንም ፤ ፲፮ ነገር፡ ግን፡ ሰው፡ በኢየሱስ፡ ክርስ ቶስ፡ በማመን፡ እንዲጸድቅ፡ እንጂ፡ በሕግ፡ ሥራ፡ እንዳይሆን፡ አውቀን÷ ሥጋን፡ የለበሰ፡ ሁሉ፡ በሕግ፡ ሥራ፡ ስለማይጸድቅ÷ እኛ፡ ራሳ ችን፡ በሕግ፡ ሥራ፡ ሳይሆን፡ በክርስቶስ፡ እም ነት፡ እንጸድቅ፡ ዘንድ፡ በክርስቶስ፡ ኢየሱስ፡ አምነናል ። ፲፯ ነገር፡ ግን፡ በክርስቶስ፡ ልንጸድቅ፡ የምንፈልግ፡ ስንሆን፡ ራሳችን፡ ደግሞ፡ ኃጢአተ ኞች፡ ሆነን፡ ከተገኘን÷ እንግዲያስ፡ ክርስቶስ፡ የኃጢአት፡ አገልጋይ፡ ነዋ ? አይደለም ። ፲፰ ያፈ ረስሁትን፡ ይህን፡ እንደ፡ ገና፡ የማንጽ፡ ከሆ ንሁ፡ ራሴ፡ ሕግ፡ ተላላፊ፡ እንድሆን፡ አስረ ዳለሁና ። ፲፱ እኔ፡ ለእግዚአብሔር፡ ሕያው፡ ሆኜ፡ እኖር፡ ዘንድ፡ በሕግ፡ በኩል፡ ለሕግ፡ ሞቼ፡ ነበ ርና ። ፳ ከክርስቶስ፡ ጋር፡ ተሰቅዬአለሁ ፤ እኔም፡ አሁን፡ ሕያው፡ ሆኜ፡ አልኖርም፡ ክርስቶስ፡ ግን፡ በእኔ፡ ይኖራል ፤ አሁንም፡ በሥጋ፡ የም ኖርበት፡ኑሮ፡ በወደደኝና፡ ስለ፡ እኔ፡ ራሱን፡ በሰጠው፡ በእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ላይ፡ በአለ፡ እምነት፡ የምኖረው፡ ነው ። ፳፩ የእግዚአብሔርን፡ ጸጋ፡ አልጥልም ፤ ጽድቅስ፡ በሕግ፡ በኩል፡ ከሆነ፡ እንኪያስ፡ ክርስቶስ፡ በከንቱ፡ሞተ ።

## ምዕራፍ፡ ፫ ።

፩ የማታስተውሉ፡ የገላትያ፡ ሰዎች፡ ሆይ÷ በዓ ይናችሁ፡ ፊት፡ ኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ እንደ፡ ተሰ ቀለ፡ ሆኖ፡ ተሥሎ፡ ነበር ፤ ለእውነት፡ እንዳ ትታዘዙ፡ አዚም፡ ያደረገባችሁ፡ ማን፡ ነው ? ፪ ይህን፡ ብቻ፡ ከእናንተ፡ እንድማር፡ እወዳለሁ ፤ በሕግ፡ ሥራ፡ ወይም፡ ከእምነት፡ ጋር፡ በሆነ፡ መስማት፡ መንፈስን፡ ተቀበላችሁን? ፫ እንዲህን፡ የማታስተውሉ፡ ናችሁ ? በመንፈስ፡ ጀምራ ችሁ፡ አሁን፡ በሥጋ፡ ትፈጸማላችሁን? ፬ በውኑ፡ ከንቱ፡ እንደ፡ ሆነስ፡ እንደዚህ፡ ያለ፡ መከራ፡ በከንቱ፡ ተቀበላችሁን? ፭ እንግዲህ፡ መንፈስን፡

፩። ፲፱ ፤ ማቴ፡ ፲፫÷፶፭ ። ፳፩ ፤ የሐዋ፡ ፱÷፴ ።
፪። ፪ ፤ ምዕ፡ ፩÷፩ ፤ የሐዋ፡ ፲፭÷፳፱ ። ፯ ፤ የሐዋ፡ ፱÷፲፭ ። ፱ ፤ ዮሐ፡ ፩÷፵፫ ። ፲ ፤ የሐዋ፡ ፲፩÷፳፱፡ ፳፬፡ ፳፱÷፲፯ ።
፲፮ ፤ የሐዋ፡ ፲፭÷፲፩ ፤ ሮሜ፡ ፫÷፳ ፡ ፳፰ ፤ መዝ፡ ፻፵፪÷፪ ። ፲፱ ፤ ሮሜ፡ ፯÷፬ ። ፳ ፤ ሮሜ፡ ፯÷፮ ፤ ዮሐ፡ ፲፯÷፳፫ ።
፳፩ ፤ ዕብ፡ ፯÷፲፩ ።
፫። ፪ ፤ ኤፌ፡ ፩÷፲፫ ።

የሚሰጣችሁ ፡ በእናንተም ፡ ዘንድ ፡ ተአምራት ፡ የሚያደርግ ፥ በሕግ ፡ ሥራ ፡ ነውን ፡ ወይስ ፡ ከእ ምነት ፡ ጋር ፡ በሆነ ፡ መስማት ፡ ነው ?

፮፤ እንዲሁ ፡ አብርሃም ፡ በእግዚአብሔር ፡ አመ ፯፤ ነና ፡ ጽድቅ ፡ ሆኖ ፡ ተቈጠረለት ። እንኪያስ ፡ ከእ ምነት ፡ የሆኑት ፡ እነዚህ ፡ የአብርሃም ፡ ልጆች ፡ ፰፤ እንደ ፡ ሆኑ ፡ እወቁ ። መጽሐፍም ፡ እግዚአብ ሔር ፡ አሕዛብን ፡ በእምነት ፡ እንዲያጸድቅ ፡ አስ ቀድሞ ፡ አይቶ ፦ በአንተ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ይባ ረካሉ ፡ ብሎ ፡ ወንጌልን ፡ ለአብርሃም ፡ አስቀ ፱፤ ድሞ ፡ ሰበከ ። እንደዚህ ፡ ከእምነት ፡ የሆኑት ፡ ከምነው ፡ ከአብርሃም ፡ ጋር ፡ ይባረካሉ ።

፲፤ ከሕግ ፡ ሥራ ፡ የሆኑት ፡ ሁሉ ፡ በእርግማን ፡ በታች ፡ ናቸውና ፤ በሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ በተጻ ፉት ፡ ሁሉ ፡ ጸንቶ ፡ የማይኖር ፡ የማያደርግም ፡ ሁሉ ፡ የተረገመ ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ ተጽፎአልና ። ፲፩፤ ጻድቅ ፡ በእምነት ፡ ይኖራል ፡ ተብሎአልና ፡ ማንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በሕግ ፡ እንዳ ፲፪፤ ይጸድቅ ፡ ግልጥ ፡ ነው ። ሕግም ፡ ከእምነት ፡ አይደለም ፡ ነገር ፡ ግን ፦ የሚያደርገው ፡ ይኖር ፲፫፤ በታል ፡ ተብሎአል ። በእንጨት ፡ የሚሰቀል ፡ ሁሉ ፡ የተረገመ ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ ተጽፎአልና ፡ ክርስቶስ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ እርግማን ፡ ሆኖ ፡ ከሕግ ፡ ፲፬፤ እርግማን ፡ ዋጀን ፤ የመንፈስን ፡ ተስፋ ፡ በእም ነት ፡ እንድንቀበል ፥ የአብርሃም ፡ በረከት ፡ ወደ ፡ አሕዛብ ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ይደርስላቸው ፡ ዘንድ ።

፲፭፤ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ እንደ ፡ ሰው ፡ ልማድ ፡ እላ ለሁ ። የሰው ፡ ስንኳ ፡ ቢሆን ፡ እርግጠኛውን ፡ ኪዳን ፡ ማንም ፡ አይንቅም ፡ ወይም ፡ አይጨም ፲፮፤ ርበትም ። ለአብርሃምና ፡ ለዘሩም ፡ የተሰፋው ፡ ቃል ፡ ተነገረ ። ስለ ፡ ብዙዎች ፡ እንደሚነገር ፦ ለዘሮቹም ፡ አይልም ፤ ስለ ፡ አንድ ፡ እንደሚ ነገር ፡ ግን ፦ ለዘርህም ፡ ይላል ፥ እርሱም ፡ ክር ፲፯፤ ስቶስ ። ይህንም ፡ እላለሁ ፤ ከአራት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዓመት ፡ በኋላ ፡ የተሰጠው ፡ ሕግ ፡ አስ ቀድሞ ፡ በእግዚአብሔር ፡ የተረጋገጠውን ፡ ኪዳን ፡ የተሰፋውን ፡ ቃል ፡ እስኪሽር ፡ ድረስ ፡ ፲፰፤ አያፈርሰም ። ርስቱ ፡ በሕግ ፡ ቢሆንስ ፡ እንግዲ ያስ ፡ በተስፋ ፡ ቃል ፡ አይሆንም ፤ በተስፋ ፡ ቃል ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአብርሃም ፡ ሰጥቶአል ።

፲፱፤ እንግዲህ ፡ ሕግ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ተስፋው ፡ የተሰጠው ፡ ዘር ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ በመካከ ለኛ ፡ እጅ ፡ በመላእክት ፡ በኩል ፡ ስለ ፡ ሕግ ፡ ፳፤ መተላለፍ ፡ ተጨመረ ። መካከለኛውም ፡ ለአ ንድ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ነው ።

፳፩፤ እንግዲህ ፡ ሕግ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የተ ስፋ ፡ ቃል ፡ የሚቃወም ፡ ነውን ? አይደለም ። ሕያው ፡ ሊያደርግ ፡ የሚቻለው ፡ ሕግ ፡ ተሰጥቶ ፡ ቢሆንስ ፡ በእውነት ፡ ጽድቅ ፡ ከሕግ ፡ በሆነ ፡ ፳፪፤ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ከማ መን ፡ የሆነው ፡ የተስፋ ፡ ቃል ፡ ለሚያምኑ ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ መጽሐፍ ፡ ከኃጢአት ፡ በታች ፡ ሁሉን ፡ ዘግቶታል ።

፳፫፤ እምነትም ፡ ሳይመጣ ፡ ሊገለጥ ፡ ላለው ፡ እም ነት ፡ ተዘግተን ፡ ከሕግ ፡ በታች ፡ እንጠበቅ ፡ ነበር ። ፳፬፤ እንደዚህ ፡ በእምነት ፡ እንጸድቅ ፡ ዘንድ ፡ ሕግ ፡ ወደ ፡ ክርስቶስ ፡ የሚያመጣ ፡ ሞግዚታችን ፡ ፳፭፤ ሆኖአል ፤ እምነት ፡ ግን ፡ መጥቶአልና ፡ ከእንግ ዲህ ፡ ወዲህ ፡ ከሞግዚት ፡ በታች ፡ አይደለንም ። ፳፮፤ በእምነት ፡ በኩል ፡ ሁላችሁ ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየ ፳፯፤ ሱስ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ናችሁና ፤ ከክ ርስቶስ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ፡ የተጠ መቃችሁ ፡ ሁሉ ፡ ክርስቶስን ፡ ለብሳችኋልና ። ፳፰፤ አይሁዳዊ ፡ ወይም ፡ የግሪክ ፡ ሰው ፡ የለም ፥ ባሪያ ፡ ወይም ፡ ጨዋ ፡ ሰው ፡ የለም ፥ ወንድም ፡ ሴትም ፡ የለም ፤ ሁላችሁ ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየ ፳፱፤ ሱስ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ናችሁና ። እናንተም ፡ የክ ርስቶስ ፡ ከሆናችሁ ፡ እንኪያስ ፡ የአብርሃም ፡ ዘር ፡ እንደ ፡ ተስፋውም ፡ ቃል ፡ ወራሾች ፡ ናችሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩፤ ነገር ፡ ግን ፡ እላለሁ ፥ ወራሹ ፡ ሕፃን ፡ ሆኖ ፡ በሚኖርበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፥ ምንም ፡ የሁሉ ፡ ጌታ ፡ ፪፤ ቢሆን ፡ ከቶ ፡ ከባሪያ ፡ አይለይም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ አባቱ ፡ እስከ ፡ ቀጠረለት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ከጠባ ፫፤ ቂዎችና ፡ ከመጋቢዎች ፡ በታች ፡ ነው ። እን ዲሁ ፡ እኛ ፡ ደግሞ ፡ ሕፃናት ፡ ሆነን ፡ ሳለን ፡ ከዓ ለም ፡ መጀመሪያ ፡ ትምህርት ፡ በታች ፡ ተገዝ ፬፤ ተን ፡ ባሪያዎች ፡ ነበርን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የዘመኑ ፡ ፍጻሜ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሴት ፡ የተወለደውን ፡ ከሕግም ፡ በታች ፡ የተወለደውን ፡ ፭፤ ልጁን ፡ ላከ ፤ እንደ ፡ ልጆች ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ፥ ፮፤ ከሕግ ፡ በታች ፡ ያሉትን ፡ ይዋጅ ፡ ዘንድ ። ልጆ ችም ፡ ስለ ፡ ሆናችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ አባ ፡ አባት ፡ ብሎ ፡ የሚጮኽ ፡ የልጁን ፡ መንፈስ ፡ ፯፤ በልባችሁ ፡ ውስጥ ፡ ላከ ። ስለዚህ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ልጅ ፡ ነህ ፡ እንጂ ፡ ባሪያ ፡ አይደለህም ፤ ልጅም ፡ ከሆንህ ፡ ደግሞ ፡ በክርስቶስ ፡ የእግዚ አብሔር ፡ ወራሽ ፡ ነህ ።

፰፤ ነገር ፡ ግን ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ሳታውቁ ፡ በባሕርያቸው ፡ አማልክት ፡ ለማይ ፱፤ ሆኑ ፡ ባሪያዎች ፡ ሆናችሁ ፡ ተገዛችሁ ፤ አሁን ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ስታውቁ ፡ ይልቁስ ፡ በእ ግዚአብሔር ፡ ስትታወቁ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ወደ ፡ ደካማ ፡ ወደሚናቅም ፡ ወደ ፡ መጀመሪያ ፡ ትም

፫። ፮፤ ዘፍጥ. ፲፭ ፥ ፮ ፤ ሮሜ ፬ ፥ ፫ ። ፰፤ ዘፍጥ. ፲፪ ፥ ፫ ። ፱፤ ሮሜ ፬ ፥ ፲፮ ። ፲፤ ዘዳግ. ፳፯ ፥ ፳፮ ። ፲፩፤ እንባ. ፪ ፥ ፬ ፤ ሮሜ ፩ ፥ ፲፯ ። ፲፪፤ ዘሌዋ. ፲፰ ፥ ፭ ። ፲፫፤ ዘዳግ. ፳፩ ፥ ፳፫ ፤ ፪ ቆሮ. ፭ ፥ ፳፩ ። ፲፮፤ ዘፍጥ. ፲፯ ፥ ፯ ፤ ፰ ። ፲፯፤ ዘፀአ. ፲፪ ፥ ፵ ። ፲፱፤ ሮሜ ፭ ፥ ፳ ፤ የሐዋ. ፯ ፥ ፶፫ ፤ ፶፫ ። ፳፩፤ ያዕ. ፬ ፥ ፳፭ ። ፳፪፤ ሮሜ ፫ ፥ ፱ ፤ ፲፩ ፥ ፴፪ ። ፳፫፤ ፩ ጴጥ. ፩ ፥ ፩ ። ፳፯፤ ዮሐ. ፩ ፥ ፲፪ ። ፳፰፤ ፩ ቆሮ. ፲፪ ፥ ፲፫ ፤ ሮሜ ፲ ፥ ፲፪ ፤ ዮሐ. ፲፯ ፥ ፳ ፤ ፳፩ ።

፬። ፫፤ ቈላ. ፪ ፥ ፰ ። ፮፤ ሮሜ ፰ ፥ ፲፭ ፤ ፲፮ ፤ ፲፯ ። ፰—፱፤ ሮሜ ፰ ፥ ፲፭—፲፯ ።

ሀርት፡እንዴት፡ትመለሳላችሁ ? እንደ፡ገና፡ ባሪያዎች፡ሆናችሁ፡ዳግመኛ፡ለዚያ፡ልትገዙ፡
፲፡ ትወዳላችሁን ? ቀንንና፡ወርን፡ዘመንንም፡
፲፩፡ ዓመትንም፡በጥንቃቄ፡ትጠብቃላችሁ ። ምና ልባት፡በከንቱ፡ስለእናንተ፡ደክሜአለሁ፡ብዬ፡ እፈራችኋለሁ ።

፲፪፡ ወንድሞች፡ሆይ ፥ እኔ፡ደግሞ፡እንደ፡እና ንተ፡ሆኜአለሁና፡—እንደ፡እኔ፡ሁኑ፡ብዬ፡እለ ምናችኋለሁ ። አንዳችም፡አልበደላችሁኝም ።
፲፫፡ በመጀመሪያ፡ወንጌልን፡በሰበክሁላችሁ፡ጊዜ፡ ከሥጋ፡ድካም፡የተነሣ፡እንደ፡ነበረ፡ታውቃ
፲፬፡ ቃላችሁ ፥ በሥጋዬም፡ፈተና፡የሆነባችሁን፡ ነገር፡አልናቃችሁትምና፡አልተጸየፋችሁትም፡ ነገር፡ግን፡እንደ፡እግዚአብሔር፡መልአክ፡ እዎን፡እንደ፡ክርስቶስ፡ኢየሱስ፡ተቀበላች
፲፭፡ ሁኝ ። እንግዲህ፡ደስ፡ማሰኘታችሁ፡ወዴት፡ አለ ? ቢቻልስ፡ዓይኖቻችሁን፡አውጥታችሁ፡
፲፮፡ በሰጣችሁኝ፡ብዬ፡እመሰክርላችኋለሁ ። እን ኪያስ፡እውነቱን፡ስለ፡ነገርኋችሁ፡ጠላት፡
፲፯፡ ሆንሁባችሁን ? በብርቱ፡ይፈልጉአችኋል ፥ ለመልካም፡አይደለም፡ነገር፡ግን፡በብርቱ፡ ትፈልጉአቸው፡ዘንድ፡በውጭ፡ሊያስቀሩአ
፲፰፡ ችሁ፡ይወዳሉ ። ነገር፡ግን፡ከእናንተ፡ዘንድ፡ በምኖርበት፡ጊዜ፡ብቻ፡ሳይሆን፡ሁልጊዜ፡ በመልካም፡ነገር፡ተፈላጊ፡ብትሆኑ፡መልካም፡
፲፱፡ ነው ። ልጆቼ፡ሆይ ፥ ክርስቶስ፡በእናንተ፡ እስኪሣል፡ድረስ፡ዳግመኛ፡ስለ፡እናንተ፡
፳፡ ምጥ፡ይዘኛል ። ስለ፡እናንተ፡አመነታለሁና፡ አሁን፡በእናንተ፡ዘንድ፡ሆኜ፡ድምፄን፡ልለ ውጥ፡በወደድሁ ።

፳፩፡ እናንተ፡ከሕግ፡በታች፡ልትኖሩ፡የምት ወዱ ፥ ሕጉን፡አትሰሙምን ? እስኪ፡ንገሩኝ ።
፳፪፡ አንዱ፡ከባሪያይቱ፡አንዱም፡ከጨዋይቱ፡ የሆኑ፡ሁለት፡ልጆች፡ለአብርሃም፡እንደ፡
፳፫፡ ነበሩት፡ተጽፎአልና ። ነገር፡ግን፡የባሪያይቱ፡ ልጅ፡እንደ፡ሥጋ፡ተወልዶአል ፥ የጨዋይቱ፡
፳፬፡ ግን፡በተስፋው፡ቃል፡ተወልዶአል ። ይህም፡ ነገር፡ምሳሌ፡ነው ፤ እነዚህ፡ሴቶች፡እንደ፡ ሁለቱ፡ኪዳኖች፡ናቸውና ። ከደብረ፡ሲና፡ የሆነችው፡እንዲቱ፡ለባርነት፡ልጆችን፡ትወ
፳፭፡ ልዳለች ፥ እርስዋም፡አጋር፡ናት ። ይህችም፡ አጋር፡በዓረብ፡ምድር፡ያለችው፡ደብረ፡ሲና፡ ናት ፤ አሁንም፡ያለችውን፡ኢየሩሳሌምን፡ ትመስላለች ፥ ከልጆችዋ፡ጋር፡በባርነት፡ናትና ።
፳፮፡ ላይኛይቱ፡ኢየሩሳሌም፡ግን፡በነጻነት፡የም ትኖር፡ናት፡እርስዋም፡እናታችን፡ናት ።
፳፯፡ አንቺ፡የማትወልጂ፡መካን ፥ ደስ፡ይበልሽ ፤ አንቺ፡አምጠሽ፡የማታውቂ ፥ እልል፡በዪና፡ ጩኺ ፤ ባል፡ካላቱ፡ይልቅ፡የብቸኛይቱ፡

ልጆች፡በዝተዋልና፡ተብሎ፡ተጽፎአል ።
፳፰፡ እኛም ፥ ወንድሞች፡ሆይ ፥ እንደ፡ይስሐቅ፡
፳፱፡ የተስፋ፡ቃል፡ልጆች፡ነን ። ነገር፡ግን፡እንደ፡ ሥጋ፡የተወለደው፡እንደ፡መንፈስ፡የተወለ ደውን፡በዚያን፡ጊዜ፡እንዳሳደደው፡ዛሬም፡
፴፡ እንዲሁ፡ነው ። ነገር፡ግን፡መጽሐፍ፡ምን፡ ይላል ? የባሪያይቱ፡ልጅ፡ከጨዋይቱ፡ልጅ፡ ጋር፡አይወርስምና፡ባሪያይቱን፡ከልጅዋ፡ጋር፡
፴፩፡ አውጣት ። ስለዚህ ፥ ወንድሞች፡ሆይ ፥ የጨ ዋይቱ፡ልጆች፡ነን፡እንጂ፡የባሪያይቱ፡አይ ደለንም ።

## ምዕራፍ፡፭ ።

፩፡ በነጻነት፡ልንኖር፡ክርስቶስ፡ነጻነት፡አወ ጣን ፤ እንግዲህ፡ጸንታችሁ፡ቁሙ፡እንደ፡ ገናም፡በባርነት፡ቀንበር፡አትያዙ ።
፪፡ እነሆ ፥ እኔ፡ጳውሎስ፡እላችኋለሁ፡— ብትገ ረዙ፡ክርስቶስ፡ምንም፡አይጠቅማችሁም ።
፫፡ ሕግንም፡ሁሉ፡እንዲፈጽም፡ግድ፡አለበት፡ብዬ፡ ለሚገረዙት፡ሁሉ፡ለእያንዳንዶች፡ደግሜ፡
፬፡ እመሰክራለሁ ። በሕግ፡ልትጸድቁ፡የምትፈ ልጉ፡ከክርስቶስ፡ተለይታችሁ፡ከጸጋው፡ወድ
፭፡ ቃችኋል ። እኛ፡በመንፈስ፡ከእምነት፡የጽ
፮፡ ድቅን፡ተስፋ፡እንጠባበቃለንና ። በክርስቶስ፡ ኢየሱስ፡ሆኖ ፥ በፍቅር፡የሚሠራ፡እምነት፡ እንጂ፡መገረዝ፡ቢሆን፡ወይም፡አለመገረዝ፡
፯፡ አይጠቅምምና ። በመልካም፡ትሮጡ፡ነበር ፤ ለእውነት፡እንዳትታዘዙ፡ማን፡ከለከላችሁ ?
፰፡ ይህ፡ማባበል፡ከሚጠራችሁ፡አልወጣም ።
፱፡፲፡ ጥቂት፡እርሾ፡ሊጡን፡ሁሉ፡ያቦካል ። የተለየ፡ ነገር፡ከቶ፡እንዳታስቡ፡እኔ፡በጌታ፡ስለ፡እና ንተ፡ታምኜአለሁ ፤ የሚያናውጣችሁ፡ማንም፡
፲፩፡ ቢኖር፡ግን፡ፍርዱን፡ሊሸከም፡ነው ። ነገር፡ ግን ፥ ወንድሞች፡ሆይ ፥ እኔ፡ገና፡እስከ፡አሁን፡ መገረዝን፡ብሰብክ፡እስከ፡አሁን፡ድረስ፡ለምን፡ ያሳድዱኛል ? እንኪያስ፡የመስቀል፡ዕንቅፋት፡
፲፪፡ ተወግዶአል ። የሚያውኩአችሁ፡ይቈረጡ ።
፲፫፡ ወንድሞች፡ሆይ ፥ እናንተ፡ለአርነት፡ተጠ ርታችኋልና ፤ ብቻ፡አርነታችሁ፡ለሥጋ፡ምክ ንያትን፡አይስጥ ፥ ነገር፡ግን፡በፍቅር፡እርስ፡
፲፬፡ በርሳችሁ፡እንደ፡ባሪያዎች፡ሁኑ ። ሕግ፡ ሁሉ፡በአንድ፡ቃል፡ይፈጸማልና ፥ እርሱም፡— ባልንጀራህን፡እንደ፡ራስህ፡ውደድ፡የሚል፡
፲፭፡ ነው ። ነገር፡ግን፡እርስ፡በርሳችሁ፡ብትነካከ ሱና፡ብትበላሉ፡እርስ፡በርሳችሁ፡እንዳትጠ ፋፉ፡ተጠንቀቁ ።

፲፮፡ ነገር፡ግን፡እላለሁ ፥ በመንፈስ፡ተመላለሱ ፥
፲፯፡ የሥጋንም፡ምኞት፡ከቶ፡አትፈጽሙ ። ሥጋ፡ በመንፈስ፡ላይ፡መንፈስም፡በሥጋ፡ላይ፡

፬። ፲፡ ቈላ. ፪፥፲፮ ። ፲፫፡ ፪ ቆሮ. ፲፪፥፯ ። ፲፬፡ ማቴ. ፲፥፵ ። ፲፯፡ ዮሐ. ፩፥፲ ። ፲፯፡ ሮሜ. ፩፥፯ ። ፲፱፡ ፩ ቆሮ. ፬፥፲፭ ። ፳፪፡ ዘፍጥ. ፲፮፥፲፭ ፤ ፳፩፥፪ ። ፳፫፡ ሮሜ ፱፥፯ ፤ ፰ ፤ ዘፍጥ. ፲፯፥፲፮ ። ፳፯፡ ኢሳ. ፶፬፥፩ ። ፳፱፡ ዘፍጥ. ፳፩፥፱ ። ፴፡ ዘፍጥ. ፳፩፥፲ ።

፭። ፩፡ ዮሐ. ፰፥፴ ። ፩፡ ሮሜ ፰፥፳፫ ፤ ፳፭ ። ፮፡ ፩ ቆሮ. ፯፥፲፱ ። ፯፡ ፩ ቆሮ. ፱፥፳፬ ። ፱፡ ፩ ቆሮ. ፭፥፮ ። ፲፡ ዮሐ. ፩፥፯ ። ፲፫፡ ፩ ቆሮ. ፰፥፱ ። ፲፫፡ ፩ ጴጥ. ፪፥፲፮ ። ፲፬፡ ዘሌዋ. ፲፱፥፲፰ ። ፲፯፡ ሮሜ ፯፥፲፰ ፤ ፳፫ ።

ይመኛልና÷እነዚህም፡እርስ፡በርሳቸው፡ይቃ ዋወማሉ፤ ስለዚህም፡የምትወዱትን፡ልታደ ፲፰ ርጉ፡አትችሉም ። በመንፈስ፡ብትመሩ፡ግን፡ ፲፱ ከሕግ፡በታች፡አይደላችሁም ። የሥጋ፡ሥራም፡ የተገለጠ፡ነው፡እርሱም፡ዝሙት÷ርኵሰት÷ ፳ መዳራት ÷ ጣዖትን፡ማምለክ ÷ ምዋርት ÷ ጥል÷ክርክር÷ቅንዓት÷ቍጣ÷አድመኛነት÷ ፳፩ መለያየት÷መናፍቅነት÷ምቀኝነት÷መግደል÷ ስካር÷ዘፋኝነት÷ይህንም፡የሚመስል፡ነው ። አስቀድሜም፡እንዳልሁ÷እንደዚህ፡ያሉትን፡ የሚያደርጉ፡የእግዚአብሔርን፡መንግሥት፡ ፳፪ አይወርሱም ። የመንፈስ፡ፍሬ፡ግን፡ፍቅር÷ ደስታ÷ሰላም÷ትዕግሥት÷ቸርነት÷በጎነት÷ ፳፫ እምነት÷የውሃት÷ራስን፡መግዛት፡ነው ። እንደዚህ፡ያሉትን፡የሚከለክል፡ሕግ፡የለም ። ፳፬ የክርስቶስ፡ኢየሱስም፡የሆኑቱ፡ሥጋን፡ከክፉ፡ መሻቱና፡ከምኞቱ፡ጋር፡ሰቀሉ ።

፳፭ በመንፈስ፡ብንኖር፡በመንፈስ፡ደግሞ፡እን ፳፮ መላለስ ። እርስ፡በርሳችን፡እየተነሣሣንና፡እየ ተቀናናን፡ስክንቱ፡አንመካ ።

ምዕራፍ፡፮ ።

፩ ወንድሞች፡ሆይ÷ሰው፡በማናቸውም፡ በደል፡ስንኳ፡ቢገኝ÷መንፈሳውያን፡የሆና ችሁ፡እናንተ፡እንደዚህ፡ያለውን፡ሰው፡በየ ውሃት፡መንፈስ፡አቅኑት፤አንተ፡ደግሞ፡እን ፪ ዳትፈተን፡ራስህን፡ጠብቅ ። ከእናንተ፡እያን ዳንዱ፡የአንዱን፡ሸክም፡ይሸከም፡እንዲሁም ፫ የክርስቶስን፡ሕግ፡ፈጽሙ ። አንዱ፡ምንም፡ ሳይሆን፡ምንም፡የሆነ፡ቢመስለው፡ራሱን፡ ፬ ያታልላልና ። ነገር፡ግን፡እያንዳንዱ፡የገዛ፡ ራሱን፡ሥራ፡ይፈትን÷ከዚያም፡በኋላ፡ስለ፡ ሌላው፡ሰው፡ያልሆነ፡ስለ፡ራሱ፡ብቻ፡የሚ ፭ መካበትን፡ያገኛል፤ እያንዳንዱ፡የገዛ፡ራሱን፡ ሸክም፡ሊሸከም፡ነውና ።

፮ ነገር፡ግን፡ቃሉን፡የሚማር፡ከሚያስተም ረው፡ጋር፡መልካምን፡ነገር፡ሁሉ፡ይካፈል ።
፯ አትሳቱ፤ እግዚአብሔር፡አይዘበትበትም ። ሰው፡የሚዘራውን፡ሁሉ፡ያንኑ፡ደግሞ፡ያጭ ፰ ዳልና፤ በገዛ፡ሥጋው፡የሚዘራ፡ከሥጋ፡መበ ስበስን፡ያጭዳልና÷በመንፈስ፡ግን፡የሚዘ ራው፡ከመንፈስ፡የዘላለምን፡ሕይወት፡ያጭ ፱ ዳል ። በንዝልም፡ለጊዜው፡እናጭዳስንና፡ መልካም፡ሥራን፡ለመሥራት፡እንታክት ። ፲ እንግዲያስ፡ጊዜ፡ካገኘን፡ዘንድ፡ለሰው፡ሁሉ፡ ይልቁንም፡ለሃይማኖት፡ቤተ፡ሰዎች፡መል ካም፡እናድርግ ።

፲፩ እንዴት፡ባሉ፡ታላላቆች፡ፊደላት፡በእጄ፡ ፲፪ እንደ፡ጻፍሁላችሁ፡እዩ ። በሥጋ፡መልካም፡ ሆነው፡ሊታዩ፡የሚወዱ፡ሁሉ፡እንድትገረዙ፡ ግድ፡አሉአችሁ÷ነገር፡ግን፡ስለ፡ክርስቶስ፡ ፲፫ መስቀል፡እንዳይሰደዱ፡ብቻ፡ነው ። በሥጋ ችሁ፡እንዲመኩ፡ልትገረዙ፡ይወዳሉ፡እንጂ፡ የተገረዙቱ፡ራሳቸው፡እንኳ፡ሕግን፡አይጠብ ፲፬ ቁም ። ነገር፡ግን፡ዓለም፡ለእኔ፡የተሰቀለበት፡ እኔም፡ለዓለም፡የተሰቀልሁበት፡ከጌታችን፡ ከኢየሱስ፡ክርስቶስ፡መስቀል፡በቀር፡ሌላ፡ ፲፭ ትምክህት፡ከእኔ፡ይራቅ ። በክርስቶስ፡ኢየ ሱስ፡አዲስ፡ፍጥረት፡መሆን፡ይጠቅማል፡ እንጂ፡መገረዝ፡ቢሆን፡ወይም፡አለመገረዝ፡ ፲፮ አይጠቅምምና ። ስዚህም፡ሥርዓት፡በሚመ ላለሱ፡ሁሉ፡ላይ፡በእግዚአብሔር፡እስራኤ ልም፡ላይ፡ሰላምና፡ምሕረት፡ይሁን ።

፲፯ እኔ፡የኢየሱስን፡ማኅተም፡በሥጋዬ፡ተሸ ክሜአለሁና፡ከእንግዲህ፡ወዲህ፡አንድ፡ስንኳ፡ አያድከመኝ ።

፲፰ ወንድሞች፡ሆይ÷የጌታችን፡የኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ጸጋ፡ከመንፈሳችሁ፡ጋር፡ይሁን ። አሜን ።

# የሐዋርያው፡የጳውሎስ፡መልእክት፡ ወደ፡ኤፌሶን፡ሰዎች ።

ምዕራፍ፡፩ ።

፩ በእግዚአብሔር፡ፈቃድ፡የኢየሱስ፡ክርስ ቶስ፡ሐዋርያ፡የሆነ፡ጳውሎስ÷በኤፌሶን፡ ላሉት፡ቅዱሳን፡በክርስቶስ፡ኢየሱስም፡ላሉት፡ ምእመናን፤
፪ ከእግዚአብሔር፡ከአባታችን፡ከጌታም፡ከኢ የሱስ፡ክርስቶስ፡ጸጋና፡ሰላም፡ለእናንተ፡ ይሁን ።

፫ በክርስቶስ፡በሰማያዊ፡ስፍራ፡በመንፈሳዊ፡ በረከት፡ሁሉ፡የባረከን፡የጌታችን፡የኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡አምላክና፡አባት፡ይባረክ ። ዓለም፡ ፬

፭። ፲፱—፳፩፤ ፩ ቆሮ· ፮÷፱፤ ፲፤ ኤፌ· ፭÷፭ ። ፳፪፤ ኤፌ· ፭÷፱ ። ፳፫፤ ፩ ጢሞ· ፩÷፱ ። ፳፬፤ ሮሜ· ፮÷፮ ። ፳፮፤ ፊልጵ· ፪÷፫ ።
፮። ፩፤ ማቴ· ፲፰÷፲፭፤ ያዕ· ፭÷፲፱ ። ፪፤ ፪ ቆሮ· ፲፫÷፭ ። ፮፤ ፩ ቆሮ· ፱÷፲፩፤፲፬ ። ፰፤ ሮሜ· ፰÷፲፫ ። ፱፤ ፪ ተሰ· ፫÷፲፫፤ ፩ ቆሮ· ፲፭÷፶፰ ። ፲፬፤ ፩ ቆሮ· ፪÷፪ ። ፲፭፤ ምዕ· ፭÷፮፤ ፩ ቆሮ· ፯÷፲፱፤ ቈላ· ፫÷፲፤፲፩ ። ፲፯፤ መዝ· ፻፴፱÷፳ ።
፩። ፪፤ ፪ ቆሮ· ፩÷፪ ።

ሳይፈጠር ÷ በፊቱ ፡ ቅዱሳንና ፡ ነውር ፡ የሌለን ፡ በፍቅር ፡ እንሆን ፡ ዘንድ ፡ በክርስቶስ ፡ መረጠን ።
፭ በበጎ ፡ ፈቃዱ ፡ እንደ ፡ ወደደ ÷ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሥራ ፡ ለእርሱ ፡ ልጆች ፡ ልንሆን ፡ አስ
፮ ቀድሞ ፡ ወሰነን ። በውድ ፡ ልጁም ፡ እንዲያው ፡ የሰጠን ፡ የጸጋው ፡ ክብር ፡ ይመሰገን ፡ ዘንድ ፡
፯ ይህን ፡ አደረገ ። በውድ ፡ ልጁም ÷ እንደ ፡ ጸጋው ፡ ባለ ፡ ጠግነት ፡ መጠን ÷ በደሙ ፡ የተ ደረገ ፡ ቤዛነታችንን ፡ አገኘን ፡ እርሱም ፡ የበደ
፰ ላችን ፡ ስርየት ። ጸጋውንም ፡ በጥበብና ፡ በአ
፱ እምሮ ፡ ሁሉ ፡ አበዛልን ። በክርስቶስ ፡ ሊያደ ርግ ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ እንደ ፡ አሳቡ ÷ የፈቃዱን ፡
፲ ምሥጢር ፡ አስታውቆናልና ፤ በዘመን ፡ ፍጻሜ ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡ አሳቡም ፡ በሰማይና ፡ በምድር ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ በክርስቶስ ፡ ለመጠ
፲፩ ቅለል ፡ ነው ። እንደ ፡ ፈቃዱ ፡ ምክር ፡ ሁሉን ፡ የሚሠራ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ አሳብ ÷ አስቀድመን ፡ የተወሰንን ፡ በክርስቶስ ፡ ደግሞ ፡ ርስትን ፡ ተቀ
፲፪ በልን ። ይኸውም ÷ በክርስቶስ ፡ አስቀድመን ፡ ተስፋ ፡ ያደረግን ፡ እኛ ፡ ለክብሩ ፡ ምስጋና ፡ እን
፲፫ ሆን ፡ ዘንድ ፡ ነው ። እናንተም ፡ ደግሞ ፡ የእ ውነትን ፡ ቃል ÷ ይኸውም ፡ የመዳናችሁን ፡ ወንጌል ÷ ሰምታችሁ ፡ ደግሞም ፡ በክርስቶስ ፡ አምናችሁ ÷ በተስፋው ፡ መንፈስ ፡ በመንፈስ ፡
፲፬ ቅዱስ ፡ ታተማችሁ ፤ እርሱም ፡ የርስታችን ፡ መያዣ ፡ ነው ÷ ለእግዚአብሔር ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ እስኪዋጅ ፡ ድረስ ÷ ይህም ፡ ለክብሩ ፡ ምስጋና ፡ ይሆናል ።

፲፭ ስለዚህ ፡ እኔ ፡ ደግሞ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ሚሆን ፡ በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ ስለ ፡ ማመንና ፡ ለቅ ዱሳን ፡ ሁሉ ፡ ስለሚሆን ፡ መውደድ ፡ ሰምቼ ÷
፲፮ ስለ ፡ እናንተ ፡ እያመሰገንሁ ፡ በጸልይ ፡ ስለ ፡ እና
፲፯ ንተ ፡ ማሳሰብን ፡ አልተውም ፤ የክብር ፡ አባት ፡ የጌታችን ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክ ፡ እር ሱን ፡ በማወቅ ፡ የጥበብንና ፡ የመገለጥን ፡ መን
፲፰፣፲፱ ፈስ ፡ እንዲሰጣችሁ ፡ እለምናለሁ ። ይህም ፡ የል ባችሁ ፡ ዓይኖች ፡ ሲበሩ ፡ የመጥራቱ ፡ ተስፋ ፡ ምን ፡ እንዲሆን ፡ በቅዱሳንም ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡ የርስት ፡ ክብር ፡ ባለ ፡ ጠግነት ፡ ምን ፡ እንዲሆን ፡ ለምናምንም ፡ ከሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ የኀይሉ ፡ ታላቅነት ፡ ምን ፡ እንዲሆን ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡
፳፣፳፩ ነው ፤ ክርስቶስንም ፡ ከሙታን ፡ ሲያስነሣው ፡ ከአለቅነትና ፡ ከሥልጣንም ፡ ከኀይልም ፡ ከጌት ነትም ፡ ሁሉ ፡ በላይና ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ሊመጣ ፡ ባለው ፡ ዓለም ፡ ደግሞ ፡ ከሚጠራው ፡ ስም ፡ ሁሉ ፡ በላይ ፡ በሰ ማያዊ ፡ ስፍራ ፡ በቀኙ ፡ ሲያስቀምጠው ፡ በክ ርስቶስ ፡ ባደረገው ፡ ሥራ ፡ የብርታቱ ፡ ጕልበት ፡
፳፪ ይታያል ፤ ሁሉንም ፡ ከእግሩ ፡ በታች ፡ አስገዘ ለት ፡ ከሁሉ ፡ በላይም ፡ ራስ ፡ እንዲሆን ፡ ለቤተ ፡
፳፫ ክርስቲያን ፡ ሰጠው ። እርስዋም ፡ አካሉና ፡ ሁሉን ፡ በሁሉ ፡ የሚሞላ ፡ የእርሱ ፡ ሙላቱ ፡ ናት ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፣፪ በበደላችሁና ፡ በኀጢአታችሁ ፡ ሙታን ፡ ነበራችሁ ፤ በእነርሱም ÷ በዚህ ፡ ዓለም ፡ እን ዳለው ፡ ኑሮ ÷ በማይታዘዙትም ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ አሁን ፡ ለሚሠራው ፡ መንፈስ ፡ አለቃ ፡ እንደ ፡ ሆነው ፡ በአየር ፡ ላይ ፡ ሥልጣን ፡ እንዳለው ፡ አለቃ ፡ ፈቃድ ÷ በፊት ፡ ተመላለሳችሁባቸው ።
፫ በእነዚህም ፡ ልጆች ፡ መካከል ፡ እኛ ፡ ሁላችን ፡ ደግሞ ÷ የሥጋችንንና ፡ የልቡናችንን ፡ ፈቃድ ፡ እያደረግን ÷ በሥጋችን ፡ ምኞት ፡ በፊት ፡ እን ኖር ፡ ነበርን ፡ እንደ ፡ ሌሎቹም ፡ ደግሞ ፡ ከፍጥረ
፬ ታችን ፡ የቍጣ ፡ ልጆች ፡ ነበርን ። ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ በምሕረቱ ፡ ባለ ፡ ጠጋ ፡ ስለ ፡ ሆነ ÷
፭ ከወደደን ፡ ከትልቅ ፡ ፍቅሩ ፡ የተነሣ ፡ በበደላ ችን ፡ ሙታን ፡ እንኳ ፡ በሆንን ፡ ጊዜ ፡ ከክርስቶስ ፡ ጋር ፡ሕይወት ፡ ሰጠን ÷ በጸጋ ፡ ድናችኋልና ÷
፮፣፯ በሚመጡ ፡ ዘመናትም ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ለእኛ ፡ ባለው ፡ ቸርነት ፡ ከሁሉ ፡ የሚበልጠውን ፡ የጸጋውን ፡ ባለ ፡ ጠግነት ፡ ያሳይ ፡ ዘንድ ÷ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አስነሣን ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስም ፡ በሰ ማያዊ ፡ ስፍራ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አስቀመጠን ።
፰ ጸጋው ፡ በእምነት ፡ አድኖአችኋልና ፤ ይህም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ስጦታ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከእና
፱ ንተ ፡ አይደለም ፤ ማንም ፡ እንዳይመካ ፡ ከሥራ ፡
፲ አይደለም ። እኛ ፡ ፍጥረቱ ፡ ነንና ፤ እንመላለ ስበት ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ አስቀድሞ ፡ ያዘ ጋጀውን ፡ መልካሙን ፡ ሥራ ፡ ለማድረግ ፡ በክ ርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ተፈጠርን ።

፲፩ ስለዚህ ፡ እናንተ ፡ አስቀድሞ ፡ በሥጋ ፡ አሕ ዛብ ፡ የነበራችሁ ÷ በሥጋ ፡ በእጅ ፡ የተገረዙ ፡ በተባሉት ፡ ያልተገረዙ ፡ የተባላችሁ ÷ ይህን ፡
፲፪ አስቡ ፤ በዚያ ፡ ዘመን ፡ ከእስራኤል ፡ መንግ ሥት ፡ ርቃችሁ ፡ ለተስፋውም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ እንግዶች ፡ ሆናችሁ ፡ በዚህም ፡ ዓለም ፡ ተስፋን ፡ አጥታችሁ ፡ ከእግዚአብሔርም ፡ ተለይታችሁ ፡
፲፫ ያለ ፡ ክርስቶስ ፡ ነበራችሁ ። አሁን ፡ ግን ፡ እና ንተ ፡ በፊት ፡ ርቃችሁ ፡ የነበራችሁ ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ሆናችሁ ፡ በክርስቶስ ፡ ደም ፡ ቀርባች
፲፬፣፲፭ ኋል ። እርሱ ፡ ሰላማችን ፡ ነውና ፤ ሁለቱን ፡ ያዋሐደ ፡ በአዋጅ ፡ የተነገሩትንም ፡ የትእዛዛትን ፡ ሕግ ፡ ሽሮ ፡ በመካከል ፡ ያለውን ፡ የጥል ፡ ግድ ግዳን ፡ በሥጋው ፡ ያፈረሰ ፤ ይህም ፡ ከሁለታ ቸው ፡ አንድን ፡ አዲስን ፡ ሰው ፡ በራሱ ፡ ይፈጥር ፡
፲፮ ዘንድ ፡ ሰላምንም ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ÷ ጥልንም ፡

፩ ። ፬ ፤ ዮሐ. ፲፭ ÷ ፲፮ ፤ ሮሜ ፰ ÷ ፳፱ ። ፮ ፤ ማቴ. ፫ ÷ ፲፯ ። ፯ ፤ ቆላ. ፩ ÷ ፲፬ ። ፲ ፤ ቆላ. ፩ ÷ ፳ ። ፲፫ ፡ ፲፬ ፤ ፪ ቆሮ. ፩ ÷ ፳፪ ። ፲፭ ፡ ፲፮ ፤ ቆላ. ፩ ÷ ፫ ፡ ፬ ። ፳ ፤ መዝ. ፻፲ ÷ ፩ ። ፳፩ ፤ ማቴ. ፳፰ ÷ ፲፰ ፤ ፊልጵ. ፪ ÷ ፱ ፤ ቆላ. ፪ ÷ ፲ ። ፳፪ ፤ መዝ. ፰ ÷ ፯ ፤ ቆላ. ፩ ÷ ፲፰ ። ፳፫ ፤ ሮሜ ፲፪ ÷ ፭ ፤ ፩ ቆሮ. ፲፪ ÷ ፲፪ ፤ ዮሐ. ፩ ÷ ፲፮ ፤ ቆላ. ፩ ÷ ፲፱ ።

፪ ። ፩ ፤ ቆላ. ፪ ÷ ፲፫ ። ፩ ፤ ቆሉ. ፩ ፤ ሮሜ ፫ ÷ ፳፱ ። ፮ ፤ ቆላ. ፫ ÷ ፩ ። ፰ ፤ ቆሉ. ፩ ። ፱ ፤ ሮሜ ፫ ÷ ፳፬ ፡ ፳፯ ፡ ፳፰ ። ፲፫ ፤ የሐዋ. ፪ ÷ ፴፱ ። ፲፭ ፤ ቆላ. ፪ ÷ ፲፬ ፤ ፪ ቆሮ. ፭ ÷ ፲፯ ።

በመስቀሉ ፡ ገድሎ ፡ ለእርሱ ፡ ሁለታቸውን ፡ በአንድ ፡ አካል ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋር ፡ ያስታ ርቅ ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ፲፯ መጥቶም ፡ ርቃችሁ ፡ ለነ በራችሁ ፡ ለእናንተ ፡ ሰላምን ፥ ቀርበው ፡ ለነበ ሩትም ፡ ሰላምን ፡ የምስራች ፡ ብሎ ፡ ሰበከ ፤ ፲፰ በእርሱ ፡ ሥራ ፡ ሁላችን ፡ በአንድ ፡ መንፈስ ፡ ወደ ፡ አብ ፡ መግባት ፡ አለንና ። ፲፱ እንግዲያስ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ከቅዱሳን ፡ ጋር ፡ ባላገሮ ችና ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤተ ፡ ሰዎች ፡ ናችሁ ፡ እንጂ ፡ እንግዶችና ፡ መጻተኞች ፡ አይደላችሁም ። ፳ በሐዋርያትና ፡ በነቢያት ፡ መሠረት ፡ ላይ ፡ ታንጻችኋል ፥ የማዕዘኑም ፡ ራስ ፡ ድንጋይ ፡ ፳፩ ክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ነው ፤ በእርሱም ፡ ሕንጻ ፡ ሁሉ ፡ እየተጋጠመ ፡ በጌታ ፡ ቅዱስ ፡ ቤተ ፡ መቅ ፳፪ ደስ ፡ እንዲሆን ፡ ያድጋል ፤ በእርሱም ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መኖሪያ ፡ ለመሆን ፡ በመንፈስ ፡ አብራችሁ ፡ ትሠራላችሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ስለዚህም ፡ አሕዛብ ፡ ስለ ፡ ሆናችሁ ፡ ስለ ፡ እና ንተ ፡ የክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ እስር ፡ የሆንሁ ፡ እኔ ፡ ጳውሎስ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እንበረከክ ፪ ለሁ ። ለእናንተ ፡ ስለ ፡ ተሰጠኝ ፡ ስለ ፡ እግዚአ ብሔር ፡ ጸጋ ፡ መጋቢነት ፡ በእርግጥ ፡ ሰምታች ፫ ኋል ፤ አስቀድሜ ፡ በአጭሩ ፡ እንደ ፡ ጻፍሁ ፥ ይህን ፡ ምሥጢር ፡ በመግለጥ ፡ አስታወቀኝ ፤ ፬ ይህንም ፡ ስታነቡ ፡ የክርስቶስን ፡ ምሥጢር ፡ እንዴት ፡ እንደማስተውል ፡ ልትመለከቱ ፡ ትች ፭፡፮ ላላችሁ ፤ ይህም ፥ አሕዛብ ፡ አብረው ፡ እንዲወ ርሱ ፥ በአንድ ፡ አካልም ፡ አብረው ፡ እንዲሆኑ ፥ በወንጌልም ፡ መስበክ ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ በሆነ ፡ የተስፋ ፡ ቃል ፡ አብረው ፡ እንዲከፈሉ ፥ ለቅዱሳን ፡ ሐዋርያትና ፡ ለነቢያት ፡ በመንፈስ ፡ አሁን ፡ እንደ ፡ ተገለጠ ፡ በሌሎቹ ፡ ትውልዶች ፡ ዘንድ ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ አልታወቀም ።

፯ እንደ ፡ ኃይሉ ፡ ሥራ ፡ እንደ ፡ ተሰጠኝም ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ ስጦታ ፡ መጠን ፡ ፰፡፱ የወንጌል ፡ አገልጋይ ፡ ሆንሁለት ። ፍለጋ ፡ የሌ ለውን ፡ የክርስቶስን ፡ ባለ ፡ ጠግነት ፡ ለአሕዛብ ፡ እሰብክ ፡ ዘንድ ፥ ሁሉንም ፡ በፈጠረው ፡ በእግዚ አብሔር ፡ ከዘላለም ፡ የተሰወረው ፡ የምሥጢር ፡ ሥርዓት ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለሁሉ ፡ አገልጥ ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ጸጋ ፡ ከቅዱሳን ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ለማ ፲ ንስ ፡ ለኔ ፡ ተሰጠ ፤ ብዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የእግዚ አብሔር ፡ ጥበብ ፡ አሁን ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በኩል ፡ በሰማያዊ ፡ ስፍራ ፡ ውስጥ ፡ ላሉት ፡ አለ ፲፩ ቆችና ፡ ሥልጣናት ፡ ትታወቅ ፡ ዘንድ ፤ ይህም ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ በጌታችን ፡ የፈጸመው ፡ ፲፪ የዘላለም ፡ አሳብ ፡ ነበረ ፥ በእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ እምነታችን ፡ በኩል ፡ በመታመን ፡ ድፍረትና ፡ ፲፫ መግባት ፡ በእርሱ ፡ አለን ። ስለዚህ ፡ ስለ ፡ እና ንተ ፡ ስላለ ፡ መከራዬ ፡ እንዳትታክቱ ፡ እለምና ችኋለሁ ፥ ክብራችሁ ፡ ነውና ።

፲፬፡፲፭ ስለዚህ ፡ ምክንያት ፡ በሰማይና ፡ በምድር ፡ ያለ ፡ አባትነት ፡ ሁሉ ፡ ከሚሰየምበት ፡ ከአብ ፡ ፲፮፡፲፯ ፊት ፡ እንበረከካለሁ ፤ በመንፈሱ ፡ በውስጥ ፡ ሰውነታችሁ ፡ በኃይል ፡ እንድትጠነከሩ ፡ ክርስ ቶስም ፡ በልባችሁ ፡ በእምነት ፡ እንዲኖር ፡ እንደ ፡ ክብሩ ፡ ባለ ፡ ጠግነት ፡ መጠን ፡ ይስጣችሁ ፤ የእና ፲፰፡፲፱ ንተ ፡ ሥርና ፡ መሠረት ፡ በፍቅር ፡ ይጸና ፡ ዘንድ ፥ ከቅዱሳን ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ስፋቱና ፡ ርዝመቱ ፡ ከፍ ታውም ፡ ጥልቅነቱም ፡ ምን ፡ ያህል ፡ መሆኑን ፡ ለማስተዋል ፥ ከመታወቅም ፡ የሚያልፈውን ፡ የክርስቶስን ፡ ፍቅር ፡ ለማወቅ ፡ ትበረቱ ፡ ዘንድ ፥ እስከ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ፍጹም ፡ ሙላት ፡ ደር ሳችሁ ፡ ትሞሉ ፡ ዘንድ ።

፳ እንግዲህ ፡ በእኛ ፡ እንደሚሠራው ፡ ኃይል ፡ መጠን ፡ ከምንለምነው ፡ ወይም ፡ ከምናስበው ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ እጅግ ፡ አብልጦ ፡ ሊያደርግ ፡ ለሚ ፳፩ ቻለው ፥ ለእርሱ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በክር ስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ እስከ ፡ ትውልዶች ፡ ሁሉ ፡ ከዘላ ለም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ክብር ፡ ይሁን ፤ አሜን ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ እንግዲህ ፡ በጌታ ፡ እስር ፡ የሆንሁ ፡ እኔ ፡ በተ ጠራችሁበት ፡ መጠራታችሁ ፡ እንደሚገባ ፡ ፪ ትመላለሱ ፡ ዘንድ ፡ እለምናችኋለሁ ፤ በትሕ ትና ፡ ሁሉና ፡ በየዋህነት ፡ በትዕግሥትም ፤ እርስ ፫ በርሳችሁ ፡ በፍቅር ፡ ታገሡ ፤ በሰላም ፡ ማሰ ሪያ ፡ የመንፈስን ፡ አንድነት ፡ ለመጠበቅ ፡ ትጉ ። ፬ በመጠራታችሁ ፡ በአንድ ፡ ተስፋ ፡ እንደ ፡ ተጠ ራችሁ ፡ አንድ ፡ አካልና ፡ አንድ ፡ መንፈስ ፡ አለ ፤ ፭ አንድ ፡ ጌታ ፡ አንድ ፡ ሃይማኖት ፡ አንዲት ፡ ጥም ፮ ቀት ፤ ከሁሉ ፡ በላይ ፡ የሚሆን ፡ በሁሉም ፡ የሚ ሠራ ፡ በሁሉም ፡ የሚኖር ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ፯ የሁሉም ፡ አባት ፡ አለ ። ነገር ፡ ግን ፡ አንዳ ፡ ክር ስቶስ ፡ ስጦታ ፡ መጠን ፡ ለእያንዳንዳችን ፡ ጸጋ ፡ ፰ ተሰጠን ። ስለዚህ ፡—

ወደ ፡ ላይ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ምርኮን ፡ ማረከ ፡
ለሰዎችም ፡ ስጦታን ፡ ሰጠ ፡

፱ ይላል ። ወደ ፡ ምድር ፡ ታችኛ ፡ ክፍል ፡ ደግሞ ፡ ወረደ ፡ ማለት ፡ ካልሆነ ፥ ይህ ፡ ወጣ ፡ ማለትስ ፡ ፲ ምን ፡ ማለት ፡ ነው ? ይህ ፡ የወረደው ፡ ሁሉን ፡ ይሞላ ፡ ዘንድ ፡ ከሰማያት ፡ ሁሉ ፡ በላይ ፡ የወ

፪። ፲፯ ፤ ኢሳ. ፶፯ ፥ ፲፱ ። ፲፰ ፤ ዮሐ. ፲፬ ፥ ፮ ። ፲፱ ፤ ዕብ. ፲፪ ፥ ፳፫ ፤ ፊልጵ. ፫ ፥ ፳ ። ፳ ፤ ማቴ. ፲፮ ፥ ፲፰ ፤ ማር. ፲፪ ፥ ፲ ። ፳፩ ፤ ፩ ቆሮ. ፫ ፥ ፲፮ ።

፫። ፩ ፤ የሐዋ. ፳፰ ፥ ፲፯ ፤ ፴ ። ፪ ፤ ቈላ. ፩ ፥ ፳፭ ። ፫ ፤ የሐዋ. ፳፮ ፥ ፲፯—፲፰ ። ፭ ፤ የሐዋ. ፲ ፥ ፳፰ ፤ ፩ ቆሮ. ፲፭ ፥ ፱ ። ፱ ፤ ሮሜ ፲፮ ፥ ፳፭ ፤ ቈላ. ፩ ፥ ፳፮ ። ፲፪ ፤ ዮሐ. ፲ ፥ ፲፰ ፤ ዕብ. ፬ ፥ ፲፮ ። ፲፫ ፤ ፪ ቆሮ. ፩ ፥ ፮ ። ፲፯ ፤ ቈላ. ፩ ፥ ፳፫ ። ፲፰ ፤ ዮሐ. ፲፬ ፥ ፳፫ ።

፬። ፩ ፤ ፩ ተሰ. ፪ ፥ ፲፪ ። ፪ ፤ ቈላ. ፫ ፥ ፲፪ ። ፬ ፤ ፭ ፤ ሚል. ፪ ፥ ፲ ፤ ፩ ቆሮ. ፰ ፥ ፮ ። ፯ ፤ ሮሜ ፲፪ ፥ ፫ ፤ ፩ ቆሮ. ፲፪ ፥ ፲፩ ። ፰ ፤ መዝ. ፷፯ ፥ ፲፰ ። ፱ ፤ ዮሐ. ፫ ፥ ፲፫ ። ፲ ፤ የሐዋ. ፪ ፥ ፴፫ ።

፲፩ ጣው ፡ ደግሞ ፡ ያው ፡ ነው ። እርሱም ፡ አንዳን ዶቹ ፡ ሐዋርያት ፥ ሌሎቹም ፡ ነቢያት ፥ ሌሎቹም ፡ ወንጌልን ፡ ሰባኪዎች ፥ ሌሎቹም ፡ እረኞችና ፡ ፲፪ ፡ ፲፫ አስተማሪዎች ፡ እንዲሆኑ ፡ ሰጠ ፤ ሁላችን ፡ የእ ግዚአብሔርን ፡ ልጅ ፡ በማመንና ፡ በማወቅ ፡ ወደ ሚገኝ ፡ አንድነት ፥ ሙሉ ፡ ሰውም ፡ ወደ ፡ መሆን ፥ የክርስቶስም ፡ ሙላቱ ፡ ወደሚሆን ፡ ወደ ፡ ሙላቱ ፡ ልክ ፡ እስክንደርስ ፡ ድረስ ፥ ቅዱሳን ፡ አገልግሎ ትን ፡ ለመሥራትና ፡ ለክርስቶስ ፡ አካል ፡ ሕንጻ ፡ ፲፬ ፍጹማን ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ። እንደ ፡ ስሕተት ፡ ሽንገላ ፡ ባለ ፡ ተንኰል ፡ በሰዎችም ፡ ማታለል ፡ ምክንያት ፡ በትምህርት ፡ ነፋስ ፡ ሁሉ ፡ እየተፍ ገመገምን ፡ ወዲያና ፡ ወዲህም ፡ እየተንሳፈፍን ፡ ፲፭ ሕፃናት ፡ መሆን ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ አይገባንም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ እውነትን ፡ በፍቅር ፡ እየያዝን ፡ በነገር ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ራስ ፡ ወደሚሆን ፡ ወደ ፡ ክር ፲፮ ስቶስ ፡ እንደግ ፤ ከእርሱም ፡ የተነሣ ፡ አካል ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ ክፍል ፡ በልክ ፡ እንደሚሠራ ፥ በተሰጠስት ፡ በጅማት ፡ ሁሉ ፡ እየተጋጠመና ፡ እየተያያዘ ፥ ራሱን ፡ በፍቅር ፡ ለማነጽ ፡ አካሉን ፡ ያሳድጋል ።

፲፯ እንግዲህ ፡ አሕዛብ ፡ ደግሞ ፡ በአእምሮአ ቸው ፡ ከንቱነት ፡ እንደሚመላለሱ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ እንዳትመላለሱ ፡ እላለሁ ፡ በጌታም ፡ ፲፰ ሆኜ ፡ እመሰክራለሁ ። እነርሱ ፡ ባስማወቃቸው ፡ ጠንቅ ፡ በልባቸውም ፡ ድንዳንነት ፡ ጠንቅ ፡ ልቡ ናቸው ፡ ጨለመ ፥ ከእግዚአብሔርም ፡ ሕይወት ፡ ፲፱ ራቁ ፤ ደንዝዘውም ፡ በመመኘት ፡ ርኵሰትን ፡ ሁሉ ፡ ለማድረግ ፡ ራሳቸውን ፡ ወደ ፡ ሴሰኝነት ፡ ፳ አሳልፈው ፡ ሰጡ ። እናንተ ፡ ግን ፡ ክርስቶስን ፡ ፳፩ እንደዚህ ፡ አልተማራችሁም ፤ በእርግጥ ፡ ሰም ታችሁታልና ፥ እውነትም ፡ በኢየሱስ ፡ እንዳለ ፡ ፳፪ በእርሱ ፡ ተምራችኋል ፤ ፊተኛ ፡ ኑሮአችሁን ፡ እያሰባችሁ ፡ እንደሚያታልል ፡ ምኞት ፡ የሚ ፳፫ ጠፋውን ፡ አሮጌውን ፡ ሰው ፡ አስወግዱ ፥ በአእ ፳፬ ምሮአችሁም ፡ መንፈስ ፡ ታደሱ ፥ ለእውነትም ፡ በሚሆኑ ፡ ጽድቅና ፡ ቅድስና ፡ እንደ ፡ እግዚአ ብሔር ፡ ምሳሌ ፡ የተፈጠረውን ፡ አዲሱን ፡ ሰው ፡ ልበሱ ።

፳፭ ስለዚህ ፡ ውሸትን ፡ አስወግዳችሁ ፥ እርስ ፡ በርሳችን ፡ ብልቶች ፡ ሆነናልና ፡ እያንዳንዳ ችሁ ፡ ከባልንጀሮቻችሁ ፡ ጋር ፡ እውነትን ፡ ተነ ፳፮ ጋገሩ ። ተቈጡ ፡ ኃጢአትንም ፡ አታድርጉ ፤ ፳፯ በቍጣችሁ ፡ ላይ ፡ ፀሐይ ፡ አይግባ ፥ ለዲያብሎ ፳፰ ስም ፡ ፈንታ ፡ አትስጡት ። የሰረቀ ፡ ከእንግ ዲህ ፡ ወዲህ ፡ አይስረቅ ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ለሚያ ፡ ፈንታ ፡ ለጐደለው ፡ የሚያከፍለው ፡ እንዲኖር ለት ፡ በገዛ ፡ እጆቹ ፡ መልካምን ፡ እየሠራ ፡ ይድ ከም ። ለሚሰሙት ፡ ጸጋን ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፥ እን ፳፱ ደሚያስፈልግ ፡ ለማነጽ ፡ የሚጠቅም ፡ ማናቸ ውም ፡ በጎ ፡ ቃል ፡ እንጂ ፡ ክፉ ፡ ቃል ፡ ከአፋችሁ ፡ ከቶ ፡ አይውጣ ። ለቤዛም ፡ ቀን ፡ የታተማችሁ ፴ በትን ፡ ቅዱሱን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንፈስ ፡ አታሳዝኑ ። መራርነትና ፡ ንዴት ፡ ቍጣም ፡ ፴፩ ጩኸትም ፡ መሳደብም ፡ ሁሉ ፡ ከክፋት ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ከእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ይወገድ ። እርስ ፡ በር ፴፪ ሳችሁም ፡ ቸሮችና ፡ ርኅሩኆች ፡ ሁኑ ፥ እግዚአ ብሔርም ፡ ደግሞ ፡ በክርስቶስ ፡ ይቅር ፡ እንዳላ ችሁ ፡ ይቅር ፡ ተባባሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ እንግዲህ ፡ እንደ ፡ ተወደዱ ፡ ልጆች ፡ እግዚ ፪ አብሔርን ፡ የምትከተሉ ፡ ሁኑ ፥ ክርስቶስም ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ወደዳችሁ ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ የመዓዛ ፡ ሽታ ፡ የሚሆንን ፡ መባንና ፡ መሥዋ ዕትን ፡ አድርጎ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ራሱን ፡ አሳልፎ ፡ እንደ ፡ ሰጠ ፡ በፍቅር ፡ ተመላለሱ ።

፫ ለቅዱሳን ፡ እንደሚገባ ፡ ግን ፡ ዝሙትና ፡ ርኵ ሰት ፡ ሁሉ ፡ ወይም ፡ መመኘት ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ፬ ከቶ ፡ አይሰማ ፤ የሚያስፍር ፡ ነገርም ፡ የስንፍና ፡ ንግግርም ፡ ወይም ፡ ዋዛ ፡ የማይገቡ ፡ ናቸውና ፡ ፭ አይሁኑ ፥ ይልቁን ፡ ምስጋና ፡ እንጂ ። ይህን ፡ እወቁ ፤ አመንዝራም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ርኵስ ፡ ወይም ፡ የሚመኝ ፡ እርሱም ፡ ጣዖትን ፡ የሚያ መልክ ፡ በክርስቶስና ፡ በእግዚአብሔር ፡ መንግ ፮ ሥት ፡ ርስት ፡ የለውም ። ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ በማ ይታዘዙት ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ ይመጣልና ፡ ማንም ፡ በከንቱ ፡ ንግግር ፡ ፯ አያታልላችሁ ። እንግዲህ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ተካ ፰ ፋዮች ፡ አትሁኑ ፤ ቀድሞ ፡ ጨለማ ፡ ነበራች ሁና ፥ አሁን ፡ ግን ፡ በጌታ ፡ ብርሃን ፡ ናችሁ ፤ ፱ ፡ ፲ የብርሃን ፡ ፍሬ ፡ በበጎነትና ፡ በጽድቅ ፡ በእውነ ትም ፡ ሁሉ ፡ ነውና ፡ ለጌታ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘ ውን ፡ እየመረመራችሁ ፥ እንደ ፡ ብርሃን ፡ ልጆች ፡ ፲፩ ተመላለሱ ፤ ፍሬም ፡ ከሌለው ፡ ከጨለማ ፡ ሥራ ፡ ጋር ፡ አትተባበሩ ፥ ይልቁን ፡ ግለጡት ፡ እንጂ ፥ ፲፪ እነርሱ ፡ በስውር ፡ ስለሚያደርጉት ፡ መናገር ፡ ፲፫ እንኳ ፡ ነውር ፡ ነውና ፤ ሁሉ ፡ ግን ፡ በብርሃን ፡ ሲገለጥ ፡ ይታያል ፤ የሚታየው ፡ ሁሉ ፡ ብርሃን ፡ ፲፬ ነውና ። ስለዚህ ፡—

> አንተ ፡ የምትተኛ ፡ ንቃ ፡ ከሙታንም ፡
> ተነሣ ፡ ክርስቶስም ፡ ያበራልሃል ፡

ይላል ።

፲፭ እንግዲህ ፡ እንደ ፡ ጥበበኞች ፡ እንጂ ፡ ጥበብ ፡ እንደሌላቸው ፡ ሳይሆን ፡ እንዴት ፡ እንድትመ ፲፮ ላለሱ ፡ በጥንቃቄ ፡ ተጠበቁ ፤ ቀኖቹ ፡ ክፉ

፬ ። ፲፩ ፤ ፩ ቆሮ ፡ ፲፪ ፥ ፳፰ ። ፲፫ ፤ ም ፡ ፩ ፥ ፳፪ ። ፲፮ ፤ ቈላ ፡ ፪ ፥ ፲፱ ። ፲፯ ፡ ፲፰ ፤ ሮሜ ፡ ፩ ፥ ፳፩ ። ፲፱ ፤ ሮሜ ፡ ፩ ፥ ፳፬ ። ፳፪ ፤ ሮሜ ፡ ፮ ፥ ፮ ። ፳፫ ፤ ሮሜ ፡ ፲፪ ፥ ፪ ። ፳፬ ፤ ዘፍጥ ፡ ፩ ፥ ፳፯ ፤ ቈላ ፡ ፫ ፥ ፲ ። ፳፭ ፤ ዘካ ፡ ፰ ፥ ፲፮ ፤ ሮሜ ፡ ፲፪ ፥ ፭ ። ፳፮ ፤ መዝ ፡ ፬ ፥ ፬ ። ፳፰ ፤ ፩ ተሰ ፡ ፬ ፥ ፲፩ ፤ ሮሜ ፡ ፲፪ ፥ ፲፫ ። ፳፱ ፤ ቈላ ፡ ፬ ፥ ፮ ። ፴ ፤ ም ፡ ፩ ፥ ፲፫ ፡ ፲፬ ፤ ኢሳ ፡ ፷፫ ፥ ፲ ። ፴፩ ፤ ቈላ ፡ ፫ ፥ ፰ ። ፴፪ ፤ ማቴ ፡ ፮ ፥ ፲፬ ፤ ቈላ ፡ ፫ ፥ ፲፪ ፡ ፲፫ ።

፭ ። ፪ ፤ ዮሐ ፡ ፲፫ ፥ ፴፬ ፤ ማቴ ፡ ፳ ፥ ፳፰ ፤ ዕብ ፡ ፲ ፥ ፲ ፤ ዘፀጥ ፡ ፳ ፥ ፴፩ ። ፭ ፤ ፩ ቆሮ ፡ ፮ ፥ ፱ ፡ ፲ ። ፮ ፤ ዮሐ ፡ ፲፪ ፥ ፴፭ ፡ ፴፮ ። ፲ ፤ ሮሜ ፡ ፲፪ ፥ ፪ ። ፲፫ ፤ ዮሐ ፡ ፫ ፥ ፳ ፡ ፳፩ ። ፲፭ ፡ ፲፮ ፤ ቈላ ፡ ፬ ፥ ፭ ።

፲፯ ዎች ፡ ናቸውና ፡ ዘመኑን ፡ ዋጁ ። ስለዚህ ፡ የጌታ ፡ ፈቃድ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስተውሉ ፡
፲፰ እንጂ ፡ ሞኞች ፡ አትሁኑ ። መንፈስ ፡ ይሙላባችሁ ፡ እንጂ ፡ በወይን ፡ ጠጅ ፡ አትስከሩ ፡
፲፱ ይህ ፡ ማባከን ፡ ነውና ፤ በመዝሙርና ፡ በዝማሬ ፡ በመንፈሳዊም ፡ ቅኔ ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ተነጋገሩ ፤ ለጌታ ፡ በልባችሁ ፡ ተቀኙና ፡ ዘምሩ ፤
፳ ሁልጊዜ ፡ ስለ ፡ ሁሉ ፡ በጌታችን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አባታችንን ፡ ስለ ፡ ሁሉ ፡ አመስግኑ ።
፳፩ ለእያንዳንዳችሁ ፡ በክርስቶስ ፡ ፍርሃት ፡ የተ
፳፪ ገዛችሁ ፡ ሁኑ ። ሚስቶች ፡ ሆይ ፥ ለጌታ ፡ እንደ
፳፫ ምትገዙ ፡ ለባሎቻችሁ ፡ ተገዙ ፤ ክርስቶስ ፡ ደግሞ ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ራስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እርሱም ፡ አካሉን ፡ የሚያድን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ባል ፡
፳፬ የሚስት ፡ ራስ ፡ ነውና ። ዳሩ ፡ ግን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ለክርስቶስ ፡ እንደምትገዛ ፡ እንዲሁ ፡ ሚስቶች ፡ ደግሞ ፡ በሁሉ ፡ ለባሎቻቸው ፡ ይገዙ ።
፳፭፡፳፮ ባሎች ፡ ሆይ ፥ ክርስቶስ ፡ ደግሞ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ እንደ ፡ ወደዳት ፡ ሚስቶቻችሁን ፡ ውደዱ ፤ በውኃ ፡ መታጠብና ፡ ከቃሉ ፡ ጋር ፡ አንጽቶ ፡ እንዲቀድሳት ፡ ስለ ፡ እርስዋ ፡ ራሱን ፡
፳፯ አሳልፎ ፡ ሰጠ ፤ እድፈት ፡ ወይም ፡ የፊት ፡ መጨማደድ ፡ ወይም ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ሳይሆንባት ፡ ቅድስትና ፡ ያለ ፡ ነውር ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ክብርት ፡ የሆነችን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ለራሱ ፡
፳፰ እንዲያቀርብ ፡ ፈለገ ። እንዲሁም ፡ ባሎች ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ገዛ ፡ ሥጋቸው ፡ አድርገው ፡ የገዛ ፡ ሚስቶቻቸውን ፡ ሊወዱአቸው ፡ ይገባቸዋል ። የገዛ ፡ ሚስቱን ፡ የሚወድ ፡ ራሱን ፡ ይወ
፳፱፡፴ ዳል ፤ ማንም ፡ የገዛ ፡ ሥጋውን ፡ የሚጠላ ፡ ከቶ ፡ የለምና ፥ ነገር ፡ ግን ፡ የአካሉ ፡ ብልቶች ፡ ስለ ፡ ሆንን ፥ ክርስቶስ ፡ ደግሞ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እንዳደረገላት ፥ ይመግበዋል ፡ ይከባከበውማል ።
፴፩ ስለዚህ ፡ ሰው ፡ አባቱንና ፡ እናቱን ፡ ይተዋል ፡ ከሚስቱም ፡ ጋር ፡ ይተባበራል ፡ ሁለቱም ፡ አንድ ፡
፴፪ ሥጋ ፡ ይሆናሉ ። ይህ ፡ ምሥጢር ፡ታላቅ ፡ ነው ፥ እኔ ፡ ግን ፡ ይህን ፡ ስለ ፡ ክርስቶስና ፡ ስለ ፡
፴፫ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እላለሁ ። ሆኖም ፡ ከእናንተ ፡ ደግሞ ፡ እያንዳንዱ ፡ የገዛ ፡ ሚስቱን ፡ እንዲሁ ፡ እንደ ፡ ራሱ ፡ አድርጎ ፡ ይውደዳት ፥ ሚስቱም ፡ ባልዋን ፡ ትፍራ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ልጆች ፡ ሆይ ፥ ለወላጆቻችሁ ፡ በጌታ ፡ ታዘዙ ፥
፪፡፫ ይህ ፡ የሚገባ ፡ ነውና ። መልካም ፡ እንዲሆንልህ ፡ ዕድሜህም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እንዲረዝም ፡ አባትህንና ፡ እናትህን ፡ አክብር ፤ እርስዋም ፡ የተስፋ ፡ ቃል ፡ ያላት ፡ ፊተኛይቱ ፡ ትእዛዝ ፡
፬ ናት ። እናንተም ፡ አባቶች ፡ ሆይ ፥ ልጆቻችሁን ፡ በጌታ ፡ ምክርና ፡ በተግሣጽ ፡ አሳድጉአቸው ፡ እንጂ ፡ አታስቈጡአቸው ።
፭ ባሪያዎች ፡ ሆይ ፥ ለክርስቶስ ፡ እንደምትታዘዙ ፡ በፍርሃትና ፡ በመንቀጥቀጥ ፡ በልባችሁ ፡ ቅንነት ፡ በሥጋ ፡ ጌቶቻችሁ ፡ ለሆኑ ፡ ታዘዙ ፤
፮ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ እንደሚያደርጉ ፡ እንደ ፡ ክርስቶስ ፡ ባሪያዎች ፡ እንጂ ፡ ለሰው ፡ ደስ ፡ እንደምታሰኙ ፡ ለታይታ ፡ የምትገዙ ፡ አት
፯ ሁኑ ። ለሰው ፡ ሳይሆን ፡ ለጌታ ፡ እንደምትገዙ ፡
፰ በትጋትና ፡ በበጎ ፡ ፈቃድ ፡ ተገዙ ፤ ባሪያ ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ጨዋ ፡ ሰው ፥ እያንዳንዱ ፡ የሚያደርገውን ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ከጌታ ፡ በብድ
፱ ራት ፡ እንዲቀበለው ፡ታውቃላችሁና ። እናንተም ፡ ጌቶች ፡ ሆይ ፥ ዛቻውን ፡ ትታችሁ ፡ እንዲሁ ፡ አድርጉላቸው ፥ በእነርሱና ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ የሚገዛው ፡ ጌታ ፡ በሰማይ ፡ እንዳለ ፡ ለሰውም ፡ ፊትም ፡ እንዳያደላ ፡ ታውቃላችሁና ።
፲ በቀረውስ ፡ በጌታና ፡ በኀይሉ ፡ ችሎት ፡ የበ
፲፩ ረታችሁ ፡ ሁኑ ። የዲያብሎስን ፡ ሽንገላ ፡ ትቃወሙ ፡ ዘንድ ፡ እንዲቻላችሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ዕቃ ፡ ጦር ፡ ሁሉ ፡ ልበሱ ።
፲፪ መጋደላችን ፡ ከደምና ፡ ከሥጋ ፡ ጋር ፡ አይደለምና ፥ ከአለቆችና ፡ ከሥልጣናት ፡ ጋር ፡ ከዚህም ፡ ከጨለማ ፡ ዓለም ፡ ገዦች ፡ ጋር ፡ በሰማያዊም ፡ ስፍራ ፡ ካለ ፡ ከክፋት ፡ መንፈሳውያን ፡ ሠራዊት ፡ ጋር ፡ ነው ፡ እንጂ ።
፲፫ ስለዚህ ፡ በክፉው ፡ ቀን ፡ ለመቃወም ፥ ሁሉንም ፡ ፈጽማችሁ ፡ ለመቆም ፡ እንድትችሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ዕቃ ፡ ጦር ፡ ሁሉ ፡ አንሡ ።
፲፬፡፲፭ እንግዲህ ፡ ወገባችሁን ፡ በእውነት ፡ ታጥቃችሁ ፥ የጽድቅንም ፡ ጥሩር ፡ ለብሳችሁ ፥ በሰላም ፡ ወንጌልም ፡ በመዘጋጀት ፡ እግሮቻችሁ ፡
፲፮ ተጫምተው ፡ ቁሙ ፤ በሁሉም ፡ ላይ ፡ ጨምራችሁ ፡ የሚንበለበሉትን ፡ የክፉውን ፡ ፍላጻዎች ፡ ሁሉ ፡ ልታጠፉ ፡ የምትችሉበትን ፡ የእ
፲፯ ምነትን ፡ ጋሻ ፡ አንሡ ፤ የመዳንንም ፡ ራስ ፡ ቍር ፡ የመንፈስንም ፡ ሰይፍ ፡ ያዙ ፡ እርሱም ፡
፲፰ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ነው ። በጸሎትና ፡ በልመናም ፡ ሁሉ ፡ ዘወትር ፡ በመንፈስ ፡ ጸልዩ ፤ በዚህም ፡ አሳብ ፡ ስለ ፡ ቅዱሳን ፡ ሁሉ ፡ እየለመ
፲፱ ናችሁ ፡ በመጽናት ፡ ሁሉ ፡ ትጉ ፤ ደግሞ ፡ የወንጌልን ፡ ምሥጢር ፡ በግልጥ ፡ እንዳስታውቅ ፡ አፌን ፡ በመክፈት ፡ ቃል ፡ ይሰጠኝ ፡ ዘንድ ፡
፳ ስለ ፡ እኔ ፡ ለምኑ ፤ ስለ ፡ ወንጌልም ፡ በሰንሰለት ፡ መልእክተኛ ፡ የሆንሁ ፥ መናገር ፡ እንደሚገባኝ ፡

፭። ፲፯፤ ቍ. ፲ ። ፲፰፤ ሉቃ. ፳፩፥፴፬፤ሮሜ. ፲፫፥፲፫ ። ፲፱፤ መዝ. ፺፭፥፩፡፪፤ ቈላ. ፫፥፲፮ ። ፳፤ ቈላ. ፫፥፲፯ ። ፳፩፤ ማቴ. ፳፥፳፮፡፳፯፤ የሐ. ፲፫፥፲፬፡፲፭ ። ፳፪፤ ዘፍጥ. ፫፥፲፮፤ ፩ ጴጥ. ፫፥፩፤ ቈላ. ፫፥፲፰ ። ፳፫፤ ፩ ቆሮ. ፲፩፥፫ ። ፳፭፤ ቈላ. ፫፥፲፱ ። ፳፯፤ መኃ. ፬፥፯፤ ቈላ. ፩፥፳፪ ። ፴፩፤ ዘፍጥ. ፪፥፳፬ ።

፮። ፩፤ ቈላ. ፫፥፳ ። ፪፤ ዘፀአ. ፳፥፲፪ ። ፬፤ ዘዳግ. ፮፥፯፤ምሳ. ፳፪፥፮፤ቈላ. ፫፥፳፩ ። ፭—፰፤ ቈላ. ፫፥፳፪—፳፭ ። ፩ ፤ ጢሞ. ፮፥፩፤ ቲቶ ፪፥፱ ። ፱፤ ቈላ. ፬፥፩ ። ፲፤ ፪ ቆሮ. ፮፥፯ ። ፲፩፤ ፩ ጴጥ. ፭፥፰ ። ፲፫፤ ፪ ቆሮ. ፲፥፬ ። ፲፬፤ ሉቃ. ፲፪፥፴፭ ። ፲፭፤ ኢሳ. ፶፪፥፯ ። ፲፮፤ ፩ ዮሐ. ፭፥፬ ። ፲፯፤ ኢሳ. ፶፱፥፲፯፤ ፩ ተሰ. ፭፥፰፤ ዕብ. ፬፥፲፪ ። ፲፰—፳፤ ቈላ. ፬፥፪—፬ ። ፳፤ ፪ ቆሮ. ፭፥፳፤ የሐዋ. ፳፰፥፳ ።

ስለ፡እርሱ፡በግልጥ፡እናገር፡ዘንድ፡ለምኑ ።

፳፩፡ ነገር፡ግን፡እናንተ፡ደግሞ፡እንዴት፡እንዳ ለሁ፡ኑሮዬን፡እንድታውቁ፡የተወደደ፡ወን ድምና፡በጌታ፡የታመነ፡አገልጋይ፡ቲኪቆስ፡

፳፪፡ ሁሉን፡ያስታውቃችኋል ፤ ወሬአችንን፡እን ድታውቁና፡ልባችሁን፡እንዲያጽናና፡ወደ፡ እናንተ፡የምልከው፡ስለዚሁ፡ምክንያት፡ነው።

፳፫፡ ከእግዚአብሔር፡አብ፡ከጌታም፡ከኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ሰላምና፡ፍቅር፡ከእምነት፡ጋር፡ ለወንድሞች፡ይሁን ።

፳፬፡ ጌታችንን፡ኢየሱስ፡ ክርስቶስን፡በስመሞተፋት፡ከሚወዱ፡ሁሉ፡ ጋር፡ጸጋ፡ይሁን ፤ አሜን ።

# የሐዋርያው፡የጳውሎስ፡መልእክት፡ ወደ፡ፊልጵስዩስ፡ሰዎች ።

ምዕራፍ፡፩ ።

፩፡ የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ባሪያዎች፡የሆኑ፡ጳው ሎስና፡ጢሞቴዎስ፡በፊልጵስዩስ፡ለሚኖሩ፡ ከኤጲስ፡ቆጶሳትና፡ከዲያቆናት፡ጋር፡በክርስ ቶስ፡ኢየሱስ፡ላሉት፡ቅዱሳን፡ሁሉ ፤

፪፡ ከእግዚአብሔር፡ከአባታችን፡ከጌታም፡ከኢ የሱስ፡ክርስቶስ፡ጸጋና፡ሰላም፡ለእናንተ፡ ይሁን ።

፫፡፬፡፭፡ ሁልጊዜ፡በጸሎቴ፡ሁሉ፡ስለ፡እናንተ፡ሁሉ፡ በደስታ፡እየጸለይሁ፥ከፊተኛው፡ቀን፡እስከ፡ ዛሬ፡ድረስ፡ወንጌልን፡በመስበክ፡አብራችሁ፡ ስለ፡ሠራችሁ፥በሰብኣችሁ፡ጊዜ፡ሁሉ፡አም

፮፡ ላኬን፡አመሰግናለሁ ። በእናንተ፡መልካምን፡ ሥራ፡የጀመረው፡እስከ፡ኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ ቀን፡ድረስ፡እንዲፈጽመው፡ይህን፡ተረድቼ

፯፡ አለሁና ፤ በእስራቴም፡ወንጌልንም፡መመከ ቻና፡መጽኛ፡በማድረግ፡ሁላችሁ፡ከእኔ፡ጋር፡ በጸጋ፡ተካፋዮች፡ስለ፡ሆናችሁ፥በልቤ፡ትኖ ራላችሁና፡ስለ፡ሁላችሁ፡ይህን፡ላስብ፡ይገ

፰፡ ባኛል ። በክርስቶስ፡ኢየሱስ፡ፍቅር፡ሁላች ሁን፡እንዴት፡እንድናፍቃችሁ፡እግዚአብ

፱፡፲፡፲፩፡ ሔር፡ምስክሬ፡ነውና ። ለእግዚአብሔርም፡ክብ ርና፡ምስጋና፡ከኢየሱስ፡ክርስቶስ፡የሚገኝ፡ የጽድቅ፡ፍሬ፡ሞልቶባችሁ፥ለክርስቶስ፡ቀን፡ ተዘጋጅታችሁ፡ቅኖችና፡አለ፡ነውር፡እንድት ሆኑ፡የሚሻለውን፡ነገር፡ፈትናችሁ፡ትወዱ፡ ዘንድ፥ፍቅራችሁ፡በእውቀትና፡በማስተዋል፡ ሁሉ፡ከፊት፡ይልቅ፡እያደገ፡እንዲበዛ፡ይህን፡ እጸልያለሁ ።

፲፪፡ ነገር፡ግን፥ወንድሞች፡ሆይ፥ይህ፡የደረሰ ብኝ፡በእውነት፡ወንጌልን፡ለማስፋት፡እንደ፡

፲፫፡ ሆነ፡ታውቁ፡ዘንድ፡እወዳለሁ ። ስለዚህም፡ እስራቴ፡ስለ፡ክርስቶስ፡እንዲሆን፡በንጉሥ፡ ዘበኞች፡ሁሉና፡በሌሎች፡ሁሉ፡ዘንድ፡ተገ

፲፬፡ ልጦአል፥በጌታም፡ካሉት፡ወንድሞች፡የሚ በዙት፡ስለ፡እስራቴ፡ታምነው፡የእግዚአብ ሔርን፡ቃል፡እንዲናገሩ፡ያለ፡ፍርሃት፡ከፊት፡ ይልቅ፡ይደፍራሉ ።

፲፭፡ አንዳንዶች፡ከቅንዓትና፡ከክርክር፡እንኳ፡ ሌሎች፡ግን፡ከበጎ፡ፈቃድ፡የተነሣ፡ክርስቶ

፲፮፡ ስን፡ይሰብኩታል ፤ እነዚህ፡ወንጌልን፡መመ ከቻ፡ለማድረግ፡እንደ፡ተሾምሁ፡አውቀው፡

፲፯፡ በፍቅር፡ይሰብካሉ ፤ እነዚያ፡ግን፡በእስራቴ፡ ላይ፡መከራን፡ሊያመጡብኝ፡መስሎአቸው፥ ለወገናቸው፡የሚጠቅም፡ፈልገው፡በቅን፡ አሳብ፡ሳይሆኑ፡ስለ፡ክርስቶስ፡ያወራሉ ።

፲፰፡ ምን፡አለ? ቢሆንም፡በሁሉ፡ጐዳና፥በማመ ካኘት፡ቢሆን፡ወይም፡በቅንነት፡ቢሆን፥ክር ስቶስ፡ይሰበካል፡ስለዚህም፡ደስ፡ብሎኛል ።

፲፱፡ ወደ፡ፊትም፡ደግሞ፡ደስ፡ይለኛል ፤ ይህ፡ በጸሎታችሁና፡በኢየሱስ፡ክርስቶስ፡መንፈስ፡ መሰጠት፡ለመዳኔ፡እንዲሆንልኝ፡አውቃለ

፳፡ ሁና፥ይህ፡ናፍቆቴ፡ተስፋዬም፡ነውና ፤ በአ ንድ፡ነገር፡እንኳ፡አላፍርም፡ነገር፡ግን፡በሕ ይወት፡ብኖር፡ወይም፡ብሞት፥ክርስቶስ፡በግ ልጥነት፡ሁሉ፡እንደ፡ወትሮው፡አሁን፡ደግሞ፡

፳፩፡ በሥጋዬ፡ይከብራል ። ለእኔ፡ሕይወት፡ክርስ

፳፪፡ ቶስ፥ሞትም፡ጥቅም፡ነውና ። ነገር፡ግን፡ በሥጋ፡መኖር፡ለእኔ፡የሥራ፡ፍሬ፡ቢሆን፥

፳፫፡ ምን፡እንድመርጥ፡አላስታውቅም ። በእነዚ ህም፡በሁለቱ፡እጨነቃለሁ ፤ ልሄድ፡ከክርስ ቶስም፡ጋር፡ልኖር፡እናፍቃለሁ፥ከሁሉ፡

፳፬፡ ይልቅ፡እጅግ፡የሚሻል፡ነውና ፤ ነገር፡ግን፡ በሥጋ፡መኖሬ፡ስለ፡እናንተ፡እጅግ፡የሚያስ

፳፭፡፳፮፡ ፈልግ፡ነው ። ይህንም፡ተረድቼ፥በእናንተ፡ ዘንድ፡እንደ፡ገና፡ስለ፡መሆኔ፥በእኔ፡መመ ኪታችሁ፡በክርስቶስ፡ኢየሱስ፡ይበዛ፡ዘንድ፥ በእምነት፡ታድጉና፡ደስ፡ይላችሁ፡ዘንድ፡እን ድኖር፡ከሁላችሁም፡ጋር፡እንድቈይ፡አው ቃለሁ ።

፳፯፡ ይሁን፡እንጂ፥መጥቼ፡በያችሁ፡ወይም፡ ብርቅ፥በአንድ፡ልብ፡ስለ፡ወንጌል፡ሃይማ ኖት፡አብራችሁ፡እየተጋደላችሁ፥በአንድ፡

[illegible footnotes]

መንፈስ፡ እንድትቆሙ፡ ስለ፡ ኑሮአችሁ፡ እሰማ፡ ዘንድ ÷ ለክርስቶስ፡ ወንጌል፡ እንደሚገባ፡ ኑሩ።

፳፰ በአንድም፡ ነገር፡ እንኳ፡ በተቃዋሚዎች፡ አት ደንግጡ ፤ ይህም፡ ለእነርሱ፡ የጥፋት ÷ ለእና ንተ፡ ግን፡ የመዳን፡ ምልክት፡ ነው ÷ ይህም፡

፳፱ ከእግዚአብሔር፡ ነው ፤ ይህ፡ ስለ፡ ክርስቶስ፡ ተሰጥቶአችኋልና ፤ ስለ፡ እርሱ፡ መከራ፡ ደግሞ፡ ልትቀበሉ፡ እንጂ፡ በእርሱ፡ ልታምኑ፡ ብቻ፡

፴ አይደለም ፤ በእኔ፡ ያያችሁት፡ አሁንም፡ በእኔ፡ እንዳለ፡ የምትሰሙት ÷ ያው፡ መጋደል፡ ደርሶ ባችኋልና ።

## ምዕራፍ፡ ፪ ።

፩ በክርስቶስም፡ አንዳች፡ ምክር፡ ቢሆን ÷ የፍ ቅር፡ መጽናናት፡ ቢሆን ÷ የመንፈስ፡ ኅብረት፡

፪ ቢሆን ÷ ምሕረትና፡ ርኅራኄ፡ ቢሆኑ ÷ ደስታ ዬን፡ ፈጽሙልኝ ፤ በአንድ፡ አሳብ፡ ተስማሙ ÷ አንድ፡ ፍቅር፡ አንድም፡ ልብ፡ አንድም፡ አሳብ፡

፫ ይሁንላችሁ ፤ ለወገኔ፡ ይጠቅማል፡ በማለት፡ ወይም፡ በከንቱ፡ ውዳሴ፡ ምክንያት፡ አንድ፡ እንኳ፡ አታድርጉ ÷ ነገር፡ ግን፡ እያንዳንዱ፡ ባል ንጀራው፡ ከራሱ፡ ይልቅ፡ እንዲሻል፡ በትሕትና፡

፬ ይቍጠር ፤ እያንዳንዱ፡ ለራሱ፡ የሚጠቅመ ውን፡ አይመልከት ÷ ለባልንጀራው፡ ደግሞ፡

፭ እንጂ ። በክርስቶስ፡ ኢየሱስ፡ የነበረ፡ ይህ፡ አሳብ፡ በእናንተ፡ ዘንድ፡ ደግሞ፡ ይሁን ።

፮ እርሱ፡ በእግዚአብሔር፡ መልክ፡ሲኖር፡ ሳለ፡ ከእግዚአብሔር፡ ጋር፡ መተካከልን፡ መቀማት፡

፯ እንደሚገባ፡ ነገር፡ አልቈጠረውም ÷ ነገር፡ ግን፡ የባሪያን፡ መልክ፡ ይዞ፡ በሰውም፡ ምሳሌ፡ ሆኖ፡

፰ ራሱን፡ ባዶ፡ አደረገ ÷ በምስሉም፡ እንደ፡ ሰው፡ ተገኝቶ፡ ራሱን፡ አዋረደ ÷ ለሞትም፡ ይኸ ውም፡ የመስቀል፡ ሞት፡ እንኳ፡ የታዘዘ፡ ሆነ ።

፱ በዚህ፡ ምክንያት፡ ደግሞ፡ እግዚአብሔር፡ ያለ ልክ፡ ከፍ፡ ከፍ፡ አደረገው ÷ ከስምም፡ ሁሉ፡

፲ በላይ፡ ያለውን፡ ስም፡ ሰጠው ፤ ይህም፡ በሰ ማይና፡ በምድር፡ ከምድርም፡ በታች፡ ያሉት፡ ሁሉ፡ በኢየሱስ፡ ስም፡ ይንበረከኩ፡ ዘንድ ÷

፲፩ መላስም፡ ሁሉ፡ ለእግዚአብሔር፡ አብ፡ ክብር፡ ኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጌታ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ይመሰ ክር፡ ዘንድ፡ ነው ።

፲፪ ስለዚህ ÷ ወዳጆቼ፡ ሆይ ÷ ሁልጊዜ፡ እንደ፡ ታዘዛችሁ ÷ በእናንተ፡ ዘንድ፡ በመኖሬ፡ ብቻ፡ ሳይሆን፡ ይልቁን፡ አሁን፡ በርቀ ÷ በፍርሃትና፡ በመንቀጥቀጥ፡ የራሳችሁን፡ መዳን፡ ፈጽሙ ፤

፲፫ ስለ፡ በጎ፡ ፈቃዱ፡ መፈለግንም፡ ማድረግንም፡ በእናንተ፡ የሚሠራ፡ እግዚአብሔር፡ ነውና ።

፲፬፡፲፭ በመጥፎና፡ በጠማማ፡ ትውልድ፡ መካከል፡ ያለ፡ ነቀፋ፡ የዋሆችም፡ ነውርም፡ የሌለባቸው፡ የእግዚአብሔር፡ ልጆች፡ እንድትሆኑ፡ ሳታን ጐራጕሩ፡ ክፉም፡ ሳታስቡ፡ ሁሉን፡ አድርጉ ፤

፲፮ በእነርሱም፡ መካከል፡ የሕይወትን፡ ቃል፡ እያ ቀረባችሁ፡ በዓለም፡ እንደ፡ ብርሃን፡ ትታያላ ችሁ ÷ ስለዚህም፡ በከንቱ፡ እንዳልሮጥሁ፡ በከ ንቱም፡ እንዳልደከምሁ፡ በክርስቶስ፡ ቀን፡ የምመካበት፡ ይሆንልኛል ።

፲፯ ነገር፡ ግን፡ በእ ምነታችሁ፡ መሥዋዕትና፡ አገልግሎት፡ ተጨ ምሬ፡ ሕይወቴ፡ እንኳ፡ ቢፈስ ÷ ደስ፡ ብሎኛል፡ ከሁላችሁም፡ ጋር፡ አብሬ፡ ደስ፡ ብሎኛል ፤

፲፰ እናንተም፡ ደግሞ፡ እንዲሁ፡ ደስ፡ ይበላችሁ፡ ከእኔም፡ ጋር፡ አብራችሁ፡ ደስ፡ ይበላችሁ ።

፲፱ ነገር፡ ግን፡ ኑሮአችሁን፡ ሳውቅ፡ እኔ፡ ደግሞ፡ ደስ፡ እንዲለኝ፡ ፈጥኜ፡ ጢሞቴዎስን፡ ልልክላ ችሁ፡ በጌታ፡ በኢየሱስ፡ ተስፋ፡ አደርጋለሁ ።

፳ እንደ፡ እርሱ፡ ያለ ÷ ስለ፡ ኑሮአችሁ፡ በቅንነት፡

፳፩ የሚጨነቅ ÷ ማንም፡ የለኝምና ፤ ሁሉ፡ የራሳ ቸውን፡ ይፈልጋሉና ÷ የክርስቶስ፡ ኢየሱስን፡

፳፪ አይደለም ። ነገር፡ ግን፡ ልጅ፡ ለአባቱ፡ እንደ ሚያገለግል፡ ከእኔ፡ ጋር፡ ሆኖ፡ ለወንጌል፡ እንደ፡

፳፫ አገለገለ፡ መፈተኑን፡ ታውቃላችሁ ። እንግዲህ፡ እንዴት፡ እንደምሆን፡ በየሁ፡ጊዜ ÷ እርሱን፡

፳፬ ቶሎ፡ እንድልክ፡ ተስፋ፡ አደርጋለሁ ፤ ራሴ፡ ደግሞ፡ ግን፡ ፈጥኜ፡ እንድመጣ፡ በጌታ፡ ታም ኜአለሁ ።

፳፭ ነገር፡ ግን፡ ወንድሜንና፡ ከእኔ፡ ጋር፡ አብሮ፡ ሠራተኛ፡ ወታደርም፡ የሚሆነውን ÷ የእናንተ፡ ግን፡ መልእክተኛ፡ የሆነውንና፡ የሚያስፈልገ ኝን፡ የሚያገለግለውን፡ አፍሮዲጡን፡ እንድልክ

፳፮ ላችሁ፡ በግድ፡ አሰባለሁ ፤ ሁላችሁን፡ ይናፍቃ ልና ÷ እንደ፡ ታመመም፡ ስለ፡ ሰማችሁ፡ ይተ

፳፯ ከዛል ። በእውነት፡ ታሞ፡ ለሞት፡ እንኳ፡ ቀርቦ፡ ነበርና ፤ ነገር፡ ግን፡ እግዚአብሔር፡ ማረው ÷ ኀዘን፡ በኀዘን፡ ላይ፡ እንዳይጨመርብኝ፡ ለእኔ፡

፳፰ ደግሞ፡ እንጂ፡ ለእርሱ፡ ብቻ፡ አይደለም ። እን ግዲህ፡ እንደ፡ ገና፡ በታዩት፡ ደስ፡ እንዲላ ችሁ፡ ለእኔም፡ ኀዘኔ፡ እንዲቃለል፡ በብዙ፡ ፍጥ

፳፱ ነት፡ እልከዋለሁ ። እንግዲህ፡ በሙሉ፡ ደስታ፡ በጌታ፡ ተቀበሉት ÷ እርሱን፡ የሚመስሉትንም፡

፴ አክብሩአቸው ፤ በእኔ፡ ዘንድ፡ ከላችሁ፡ አገል ግሎት፡ እናንተ፡ በሌላችሁ፡ የጐደለኝን፡ እን ዲፈጽም ÷ በነፍሱ፡ ተወራርዶ፡ ከጌታ፡ ሥራ፡ የተነሣ፡ እስከ፡ ሞት፡ ቀርቦአልና ።

## ምዕራፍ፡ ፫ ።

፩ በቀረውስ ÷ ወንድሞቼ፡ ሆይ ÷ በጌታ፡ ደስ፡ ይበላችሁ ። ስለ፡ አንድ፡ ነገር፡ መልሼ፡ ልጽ

፩። ፳፪ ፤ ማቴ· ፭ ÷ ፲፩ ። ፴ ፤ የሐዋ· ፲፮ ÷ ፲፱—፳፬ ።

፪። ፫ ፤ ገላ· ፭ ÷ ፳፮ ፤ ሮሜ ፲፪ ÷ ፲ ። ፬ ፤ ፩ ቆሮ· ፲ ÷ ፳፬ ፤ ሮሜ ፲፭ ÷ ፪ ። ፭ ፤ ማቴ· ፲፩ ÷ ፳፱ ። ፮ ፤ ዮሐ· ፩ ÷ ፩ ፤ ፪ ፤ ፩ ÷ ፲፭ ፤ ቈላ· ፩ ÷ ፲፭ ። ፯ ፤ ፪ ቆሮ· ፰ ÷ ፱ ፤ ኢሳ· ፶፫ ÷ ፫ ፤ ማቴ· ፳ ÷ ፳፰ ፤ ገላ· ፬ ÷ ፬ ። ፰ ፤ ማቴ· ፳፮ ÷ ፴፱ ፤ ዕብ· ፭ ÷ ፰ ፤ ፲፪ ÷ ፪ ። ፱ ፤ ኢሳ· ፶፪ ÷ ፲፫ ፤ የሐዋ· ፪ ÷ ፴፫ ፤ ኤፌ· ፩ ÷ ፳፩ ። ፲ ፤ ኢሳ· ፵፭ ÷ ፳፫ ፤ ሮሜ ፲፬ ÷ ፲፩ ። ፲፩ ፤ ዮሐ· ፲ ÷ ፳፱ ። ፲፪ ፤ መዝ· ፪ ÷ ፲፩ ። ፲፫ ፤ ፩ ቆሮ· ፲፭ ÷ ፲ ። ፲፬ ፤ ዘዳግ· ፴፪ ÷ ፭ ፤ ማቴ· ፭ ÷ ፲፬ ። ፲፭ ፤ ኢሳ· ፵፱ ÷ ፬ ፤ ፩ ተሰ· ፪ ÷ ፲፱ ። ፲፯ ፤ ሮሜ ፲፭ ÷ ፲፮ ፤ ፪ ጢሞ· ፬ ÷ ፮ ። ፳ ፤ ፩ ቆሮ· ፲፮ ÷ ፲ ። ፳፪ ፤ ፩ ጢሞ· ፩ ÷ ፪ ።

ፍላችሁ፡እኔን፡አይታክተኝም፡ለእናንተ፡ግን፡
ደኅና፡ነው።

፪ ከውሾች፡ተጠበቁ፣ከክፉዎችም፡ሠራተ
ኞች፡ተጠበቁ፣ከሐሰተኛም፡መገረዝ፡ተጠ
፫ በቁ። እኛ፡በመንፈስ፡እግዚአብሔርን፡የምና
መልክ፡በክርስቶስ፡ኢየሱስም፡የምንመካ፡በሥ
፬ ጋም፡የማንታመን፡እኛ፡የተገረዝን፡ነንና። እኔ፡
ግን፡በሥጋ፡ደግሞ፡የምታመንበት፡አለኝ።
ሌላ፡ሰው፡ማንም፡ቢሆን፡በሥጋ፡የሚታመ
ንበት፡እንዳለው፡ቢመስለው፣እኔ፡እበልጠ
፭ ዋለሁ። በስምንተኛው፡ቀን፡የተገረዝሁ፣
ከእስራኤል፡ትውልድ፣ከብንያም፡ወገን፣
ከዕብራውያን፡ዕብራዊ፡ነኝ፤ስለ፡ሕግ፡ብት
፮ ጠይቁ፣ፈሪሳዊ፡ነበርሁ፤ስለ፡ቅንዓት፡ብት
ጠይቁ፣ቤተ፡ክርስቲያንን፡አሳዳጅ፡ነበርሁ፤
በሕግ፡ስለሚገኝ፡ጽድቅ፡ብትጠይቁ፣ያለ፡
፯ ነቀፋ፡ነበርሁ። ነገር፡ግን፡ለእኔ፡ረብ፡የነበ
ረውን፡ሁሉ፡ስለ፡ክርስቶስ፡እንደ፡ጉዳት፡
፰፡፱ ቈጥሬዋለሁ። አዎን፣በእውነት፡ከሁሉ፡
ይልቅ፡ስለሚበልጥ፡ስለ፡ክርስቶስ፡ኢየሱስ፡
ስለ፡ጌታዬ፡እውቀት፡ነገር፡ሁሉ፡ጉዳት፡
እንዲሆን፡እቈጥራለሁ፤ስለ፡እርሱ፡ሁሉን፡
ተጐዳሁ፣ክርስቶስንም፡አገኝ፡ዘንድ፣በክር
ስቶስም፡በማመን፡ያለው፡ጽድቅ፡ማለት፡በእ
ምነት፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ያለው፡ጽድቅ፡
እንጂ፡ከሕግ፡ለእኔ፡ያለው፡ጽድቅ፡ሳይሆ
ንልኝ፣በእርሱ፡እገኝ፡ዘንድ፡ሁሉን፡እንደ፡
፲፡፲፩ ጕድፍ፡እቈጥራለሁ፤እርሱንና፡የትንሣኤ
ውን፡ኃይል፡እንዳውቅ፣በመከራውም፡እን
ድካፈል፣ወደ፡ሙታንም፡ትንሣኤ፡ልደርስ፡
ቢሆንልኝ፣በሞቱ፡እንድመስለው፡እመኛ
ለሁ።

፲፪ አሁን፡እንዳገኘሁ፡ወይም፡አሁን፡ፍጹም፡
እንደ፡ሆንሁ፡አይደለም፤ነገር፡ግን፡ስለ፡እርሱ፡
በክርስቶስ፡ኢየሱስ፡የተያዝሁበትን፡ያን፡
፲፫ ደግሞ፡እይዛለሁ፡ብዬ፡እፈጥናለሁ። ወንድ
ሞች፡ሆይ፣እኔ፡ገና፡እንዳልያዝሁት፡እቈጥ
ራለሁ፤ነገር፡ግን፡አንድ፡ነገር፡አደርጋለሁ፤
በኋላዬ፡ያለውን፡እየረሳሁ፡በፊቴ፡ያለውን፡ለመ
፲፬ ያዝ፡እዘረጋለሁ፣በክርስቶስ፡ኢየሱስ፡ከፍ፡ከፍ፡
ያለውን፡የእግዚአብሔርን፡መጥራት፡ዋጋ፡
፲፭ እንዳገኝ፡ምልክትን፡እፈጥናለሁ። እንግዲህ፡
ፍጹማን፡የሆንን፡ሁላችን፡ይህን፡እናስብ፤
በአንዳች፡ነገርም፡ልዩ፡አሳብ፡ቢኖራችሁ፣
እግዚአብሔር፡ይህን፡ደግሞ፡ይገልጥላችኋል፤
፲፮ ሆኖም፡በደረስንበት፡በዚያ፡እንመላለስ።
፲፯ ወንድሞች፡ሆይ፣እኔን፡የምትመስሉ፡
ሁኑ፣እኛም፡እንደ፡ምሳሌ፡እንደምንሆንላ
ችሁ፣እንዲሁ፡የሚመላለሱትን፡ተመልከቱ።
፲፰ ብዙዎች፡ለክርስቶስ፡መስቀል፡ጠላቶቹ፡
ሆነው፡ይመላለሳሉና፤ብዙ፡ጊዜ፡ስለ፡እነ
ርሱ፡አልኋችሁ፣አሁንም፡እንኳ፡እያለቀ
፲፱ ስሁ፡እላለሁ። መጨረሻቸው፡ጥፋት፡ነው፣
ሆዳቸው፡አምላካቸው፡ነው፣ክብራቸው፡
በነውራቸው፡ነው፣አሳባቸው፡ምድራዊ፡
፳ ነው። እኛ፡አገራችን፡በሰማይ፡ነውና፣ከዚ
ያም፡ደግሞ፡የሚመጣ፡መድኃኒትን፡እርሱ
ንም፡ጌታን፡ኢየሱስ፡ክርስቶስን፡እንጠባበ
፳፩ ቃለን፤እርሱም፡ሁሉን፡እንኳ፡ለራሱ፡ሊያ
ስገዛ፡እንደሚችልበት፡አሠራር፣ክቡር፡ሥጋ
ውን፡እንዲመስል፡የተዋረደውን፡ሥጋችንን፡
ይለውጣል።

## ምዕራፍ፡፬።

፩ ስለዚህ፣የምወዳችሁና፡የምናፍቃችሁ፣
ደስታዬና፡አክሊሌ፡የምትሆኑ፡ወንድሞቼ፡
ሆይ፣እንዲሁ፡በጌታ፡ቁሙ፣ወዳጆች፡ሆይ።
፪ በአንድ፡አሳብ፡በጌታ፡እንዲስማሙ፡ኤዎ
ድያንን፡እመክራለሁ፡ሲንጤኪንንም፡እመክራ
፫ ለሁ። አንተም፡ደግሞ፡በሥራዬ፡አብረህ፡የተ
ጠመድህ፡እውነተኛ፡ሆይ፣እንድታግዛቸው፡
እለምንሃለሁ፤ስሞቻቸው፡በሕይወት፡መጽ
ሐፍ፡ከተጻፉት፡ከቀሌምንጦስና፡ደግሞ፡ከእኔ፡
ጋር፡አብረው፡ከሠሩት፡ከሌሎቹ፡ጋር፡በወ
ንጌል፡ከእኔ፡ጋር፡አብረው፡ተጋድለዋልና።
፬ ሁልጊዜ፡በጌታ፡ደስ፡ይበላችሁ፤ደግሜ፡
፭ እላለሁ፣ደስ፡ይበላችሁ። ገርነታችሁ፡ለሰው፡
፮ ሁሉ፡ይታወቅ። ጌታ፡ቅርብ፡ነው። በነገር፡
ሁሉ፡በጸሎትና፡በምልጃ፡ከምስጋና፡ጋር፡
በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ልመናችሁን፡አስታ
፯ ውቁ፡እንጂ፡በአንዳች፡አትጨነቁ። አእም
ሮንም፡ሁሉ፡የሚያልፍ፡የእግዚአብሔር፡
ሰላም፡ልባችሁንና፡አሳባችሁን፡በክርስቶስ፡
ኢየሱስ፡ይጠብቃል።
፰ በቀረውስ፣ወንድሞች፡ሆይ፣እውነተኛ፡
የሆነውን፡ነገር፡ሁሉ፣ጭምትነት፡ያለበትን፡
ነገር፡ሁሉ፣ጽድቅ፡የሆነውን፡ነገር፡ሁሉ፣
ንጹሕ፡የሆነውን፡ነገር፡ሁሉ፣ፍቅር፡ያለበ
ትን፡ነገር፡ሁሉ፣መልካም፡ወሬ፡ያለበትን፡
ነገር፡ሁሉ፣በጎነት፡ቢሆን፡ምስጋናም፡ቢሆን፣
፱ እነዚህን፡አስቡ፤ከእኔ፡የተማራችሁትንና፡
የተቀበላችሁትን፡የሰማችሁትንም፡ያያችሁ
ትንም፡እነዚህን፡አድርጉ፤የሰላምም፡አም
ላክ፡ከእናንተ፡ጋር፡ይሆናል።

፫። ፪፤ መዝ. ፳፪፥፲፮፤ ራእ. ፳፪፥፲፭፤ ፪ ቆሮ. ፲፩፥፲፫። ፫፤ ሮሜ. ፪፥፳፱፤ ዮሐ. ፬፥፳፫፤ ፳፬። ፭፤ ዘፍጥ. ፲፯፥፲፪፤ ፲፱፤ ፪ ቆሮ. ፲፩፥፳፪፤ ሮሜ. ፲፩፥፩፤ የሐዋ. ፳፫፥፮። ፮፤ የሐዋ. ፳፪፥፫፤ ፬። ፯፤ ማቴ. ፲፫፥፵፬፤ ፵፮። ፰፤ ኢሳ. ፶፫፥፲፩፤ ዮሐ. ፲፯፥፫። ፱፤ ሮሜ. ፫፥፳፩፤ ፳፪። ፲፤ ሮሜ. ፮፥፭፤ ፩ ጴጥ. ፬፥፲፫። ፲፫፤ ሉቃ. ፱፥፷፪። ፲፬፤ ፩ ቆሮ. ፱፥፳፬። ፲፭፤ ፩ ቆሮ. ፲፬፥፳፤ ፩ ጴጥ. ፭፥፫። ፲፮፤ ፩ ቆሮ. ፩፥፲፫፤ ፪ ቆሮ. ፲፮፥፲፫። ፲፯፤ ሮሜ. ፲፮፥፲፯። ፳፤ ኤፌ. ፪፥፲፱፤ ዮሐ. ፲፬፥፫፤ ቲቶ ፪፥፲፫። ፳፩፤ ፩ ቆሮ. ፲፭፥፵፫፤ ፵፱፤ ኤፌ. ፩፥፲፱።

፬። ፩፤ ፩ ተሰ. ፪፥፲፱፤ ፳። ፫፤ ሉቃ. ፲፥፳፤ ራእ. ፲፫፥፰። ፭፤ ቲቶ ፫፥፪፤ ራእ. ፳፪፥፳። ፮፤ ማቴ. ፮፥፳፭፤ ፩ ጴጥ. ፭፥፯። ፯፤ ዮሐ. ፲፬፥፳፯።

፲ ነገር ፡ ግን ፡ አሁን ፡ ከጊዜ ፡ በኋላ ፡ ስለ ፡ እኔ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ልታስቡ ፡ ስለ ፡ ጀመራችሁ ፥ በጌታ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፤ ጊዜ ፡ አጣችሁ ፡ እንጂ ፡ ፲፩ ማሰብስ ፡ ታስቡ ፡ ነበር ። ይህን ፡ ስል ፡ ስለ ፡ ጕድ ለት ፡ አልልም ፤ የምኖርበት ፡ ኑሮ ፡ ይበቃኛል ፡ ፲፪ ማለትን ፡ ተምሬአለሁና ። መዋረድንም ፡ አው ቃለሁ ፡ መብዛትንም ፡ አውቃለሁ ፤ በእያንዳ ንዱ ፡ ነገር ፡ በነገርም ፡ ሁሉ ፡ መጥገብንና ፡ መራ ብንም ፡ መብዛትንና ፡ መጕደልን ፡ ተምሬአለሁ ። ፲፫ ኃይልን ፡ በሚሰጠኝ ፡ በክርስቶስ ፡ ሁሉን ፡ እች ላለሁ ።

፲፬ ሆኖም ፡ በመከራዬ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ስለ ፡ ተካፈ ፲፭ ላችሁ ፡ መልካም ፡ አደረጋችሁ ። የፊልጵስዩስ ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ፥ ወንጌል ፡ በመጀመሪያ ፡ ሲሰበክ ፥ ከመቄዶንያ ፡ በወጣሁ ፡ ጊዜ ፥ ከእናንተ ፡ ብቻ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በመስጠትና ፡ በመቀበል ፡ ስሌት ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ እንዳልተካፈለች ፡ ፲፮ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ታውቃላችሁ ፤ በተሰሎንቄ ፡ እንኳ ፡ ሳለሁ ፥ አንድ ፡ ጊዜና ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ያስፈለገኝን ፡ ሰዳችሁልኝ ፡ ነበርና ። በስሌታ ፲፯ ችሁ ፡ የሚበዛውን ፡ ፍሬ ፡ እንጂ ፡ ስጦታውን ፡ ፈላጊ ፡ አይደለሁም ። ነገር ፡ ግን ፡ ሁሉ ፡ አለኝ ፡ ፲፰ ይበዛልኝማል ፤ የመዓዛ ፡ ሽታና ፡ የተወደደ ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆነውን ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡ ስጦታችሁን ፡ ከአፍሮ ዲጡ ፡ ተቀብዬ ፡ ተሞልቼአለሁ ። አምላኬም ፡ ፲፱ እንደ ፡ ባለ ፡ ጠግነቱ ፡ መጠን ፡ በክብር ፡ በክርስ ቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ የሚያስፈልጋችሁን ፡ ሁሉ ፡ ይሞ ላባችኋል ። ለአምላካችንና ፡ ለአባታችንም ፡ ፳ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ ክብር ፡ ይሁን ፤ አሜን ።

፳፩ ለቅዱሳን ፡ ሁሉ ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ሰላ ምታ ፡ አቅርቡ ። ከእኔ ፡ ጋር ፡ ያሉት ፡ ወንድ ፳፪ ሞች ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡላችኋል ። ቅዱሳን ፡ ሁሉ ፡ ይልቁንም ፡ ከቄሣር ፡ ቤት ፡ የሆኑት ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡላችኋል ።

፳፫ የጌታችን ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋ ፡ ከመ ንፈሳችሁ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፤ አሜን ።

# የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ቈላስይስ ፡ ሰዎች ።

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ በእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስ ቶስ ፡ ሐዋርያ ፡ የሆነ ፡ ጳውሎስ ፡ ጢሞቴዎስም ፡ ፪ ወንድሙ ፥ በቈላስይስ ፡ ለሚኖሩ ፡ ቅዱሳንና ፡ ለክርስቶስ ፡ ለታመኑ ፡ ወንድሞች ፤

ከእግዚአብሔር ፡ ከአባታችን ፡ ከጌታም ፡ ከኢ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋና ፡ ሰላም ፡ ይሁን ።

፫፡፬፡፭ ስለ ፡ እናንተ ፡ ስንጸልይ ፥ በሰማይ ፡ ከተዘ ጋጀላችሁ ፡ ተስፋ ፡ የተነሣ ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየ ሱስ ፡ ስለ ፡ እምነታችሁ ፡ ስለ ቅዱሳንም ፡ ሁሉ ፡ ስላላችሁ ፡ ፍቅር ፡ ሰምተን ፥ የጌታችንን ፡ የኢ የሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ አባት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ሁልጊዜ ፡ እናመሰግናለን ፤ ስለዚህም ፡ ተስፋ ፡ በወንጌል ፡ እውነት ፡ ቃል ፡ አስቀድማችሁ ፡ ፮ ሰማችሁ ። ይህም ፡ በዓለም ፡ ሁሉ ፡ ደግሞ ፡ እንዳለ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ደርሶአል ፥ የእግዚአ ብሔርንም ፡ ጸጋ ፡ በእውነት ፡ ከሰማችሁበትና ፡ ከወቃችሁበት ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፥ በእናንተ ፡ ደግሞ ፡ እንዳለ ፡ እንዲሁ ፡ በዓለም ፡ ፍሬ ፡ ያፈራል ፡ ያድ ፯ ግማል ። ከተወደደ ፡ ከእኛም ፡ ጋር ፡ አብሮ ፡ ባሪያ ፡ ከሆነው ፡ ከኤጳፍራ ፡ እንዲሁ ፡ ተማራ ችሁ ፥ እርሱም ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ታማኝ ፡ የክር ፰ ስቶስ ፡ አገልጋይ ፡ ነው ። ደግሞም ፡ በመንፈስ ፡ ስለሚሆን ፡ ስለ ፡ ፍቅራችሁ ፡ አስታወቀን ።

፱ ስለዚሁ ፡ እኛ ፡ ደግሞ ፡ ይህን ፡ ከሰማንበት ፡ ቀን ፡ ጀምረን ፡ የፈቃዱ ፡ እውቀት ፡ መንፈሳዊ ፡ ጥበብንና ፡ አእምሮን ፡ ሁሉ ፡ እንዲሞላባችሁ ፡ እየለመንን ፥ ስለ ፡ እናንተ ፡ ጸሎትን ፡ አልተው ፲፡፲፩ ንም ፤ በበጎ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ፍሬ ፡ እያፈራችሁ ፡ ፲፪ በእግዚአብሔርም ፡ እውቀት ፡ እያደጋችሁ ፥ ከደስታም ፡ ጋር ፡ በሁሉ ፡ ለመጽናትና ፡ ለመታ ገሥ ፡ እንደ ፡ ክብሩ ፡ ኃይልበት ፡ መጠን ፡ በኃይል ፡ ሁሉ ፡ እየበረታችሁ ፥ በቅዱሳንም ፡ ርስት ፡ በብ ርሃን ፡ እንድንካፈል ፡ ያበቃንን ፡ አብን ፡ እያመ ሰገናችሁ ፥ በነገር ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ልታሰኙ ፡ ለጌታ ፡ እንደሚገባ ፡ ትመላለሱ ፡ ዘንድ ፡ እንለምናለን ።

፲፫፡፲፬ እርሱ ፡ ከጨለማ ፡ ሥልጣን ፡ አዳነን ፥ ቤዛነቱ ንም ፡ እርሱንም ፡ የኃጢአትን ፡ ስርየት ፡ ወዳ ገኘንበት ፡ ወደ ፡ ፍቅሩ ፡ ልጅ ፡ መንግሥት ፡ አፈለሰን ።

፲፭፡፲፮ እርሱም ፡ የማይታይ ፡ አምላክ ፡ ምስሌ ፡ ነው ፤ የሚታዩትና ፡ የማይታዩትም ፥ ዙፋናት ፡ ቢሆኑ ፡ ወይም ፡ ጌትነት ፡ ወይም ፡ አለቅነት ፡ ወይም ፡ ሥልጣናት ፥ በሰማይና ፡ በምድር ፡ ያሉት ፡ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ ተፈጥረዋልና ፡ ከፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ በፊት ፡ በኵር ፡ ነው ፤ ሁሉ ፡ በእርሱና ፡ ለእርሱ ፡ ተፈጥሮአል ፤ እርሱም ፡ ከሁሉ ፡ በፊት ፡ ነው ፡ ፲፯

፬። ፲ ፪ ቆሮ. ፲፩ ፥ ፱ ። ፲፩ ፩ ጢሞ. ፮ ፥ ፮ ። ፲፫ ኢሳ. ፵ ፥ ፳፱—፴፩ ፤ ፪ ቆሮ. ፲፪ ፥ ፱ ፡ ፲ ። ፲፭ ቍ. ፲ ፤ የሐዋ. ፲፯ ፥ ፩ ። ፲፰ ፊል. ፪ ፥ ፳፭ ፤ ኤፌ. ፭ ፥ ፪ ፤ ዕብ. ፲፫ ፥ ፲፮ ። ፲፱ ፪ ቆሮ. ፱ ፥ ፰ ። ፳ ገላ. ፩ ፥ ፬ ፡ ፭ ።

፩። ፩ ፡ ፪ ፤ ኤፌ. ፩ ፥ ፩ ፡ ፪ ፤ ፊልጵ. ፩ ፥ ፪ ። ፫ ፡ ፬ ፤ ኤፌ. ፩ ፥ ፲፭ ፡ ፲፮ ። ፱ ፤ ኤፌ. ፩ ፥ ፲፮ ፤ ፊልጵ. ፩ ፥ ፱ ። ፲ ኤፌ. ፬ ፥ ፩ ። ፲፩ ኤፌ. ፫ ፥ ፲፮ ፤ ፬ ፥ ፪ ። ፲፫ ሉቃ. ፳፪ ፥ ፶፫ ፤ ኤፌ. ፮ ፥ ፲፪ ። ፲፬ ኤፌ. ፩ ፥ ፯ ። ፲፭ ፪ ቆሮ. ፬ ፥ ፬ ፤ ዕብ. ፩ ፥ ፫ ። ፲፮ ዮሐ. ፩ ፥ ፫ ። ፲፯ ዮሐ. ፰ ፥ ፶፰ ።

ሁሉም ፡ በእርሱ ፡ ተጋጥሞአል ። ፲፰ እርሱም ፡ የአካሉ ፡ ማለት ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ራስ ፡ ነው ፤ እርሱም ፡ በሁሉ ፡ ፊተኛ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፥ መጀመሪያ ፡ ከሙታንም ፡ በኵር ፡ ነው ። ፲፱ እግዚአብሔር ፡ ሙላቱ ፡ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ እንዲኖር ፥ ፳ በእርሱም ፡ በኵል ፡ በመስቀሉ ፡ ደም ፡ ሰላም ፡ አድርጎ ፡ በምድር ፡ ወይም ፡ በሰማያት ፡ ያሉትን ፡ ሁሉ ፡ ለራሱ ፡ እንዲያስታርቅ ፡ ፈቅዶአልና ።

፳፩ እናንተንም ፡ ነውርና ፡ ነቀፋ ፡ የሌላችሁና ፡ ቅዱሳን ፡ አድርጎ ፡ በእርሱ ፡ ፊት ፡ ያቀርባችሁ ፡ ዘንድ ፥ በፊት ፡ የተለያችሁትን ፡ ከፉ ፡ ሥራችሁንም ፡ በማድረግ ፡ በአሳባችሁ ፡ ጠላቶች ፡ የነበራችሁትን ፡ አሁን ፡ በሥጋው ፡ ሰውነት ፡ ፳፪ በሞቱ ፡ በኵል ፡ አስታረቃችሁ ። ፳፫ ይህም ፥ ተመሥርታችሁና ፡ ተደላድላችሁ ፡ ከሰማችሁትም ፡ ከወንጌል ፡ ተስፋ ፡ ሳትናወጡ ፥ በሃይማኖት ፡ ጸንታችሁ ፡ብትኖሩ ፡ ይሆናል ፤ ያም ፡ ወንጌል ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡ ባለው ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ የተሰበከ ፡ ነው ፥ እኔም ፡ ጳውሎስ ፡ የእርሱ ፡ አገልጋይ ፡ ሆንሁ ።

፳፬ አሁን ፡ በመከራዬ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፥ ስለ ፡ አካሉም ፡ ማለት ፡ ስለ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በሥጋዬ ፡ በክርስቶስ ፡ መከራ ፡ የጐደለውን ፡ እፈጽማለሁ ። ፳፭ ስለ ፡ እናንተ ፡ እንደ ፡ ተሰጠኝ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መጋቢነት ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ፈጽሜ ፡ እንድሰብክ ፡ እኔ ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አገልጋይ ፡ ሆንሁ ፤ ፳፮ ይህም ፡ ቃል ፡ ከዘላለምና ፡ ከትውልዶች ፡ ጀምሮ ፡ ተሰውሮ ፡ የነበረ ፡ ምሥጢር ፡ ነው ፥ አሁን ፡ ግን ፡ ለቅዱሳኑ ፡ ተገልጦአል ፤ ፳፯ ለእነርሱም ፡ እግዚአብሔር ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡ የዚህ ፡ ምሥጢር ፡ ክብር ፡ ባለ ፡ ጠግነት ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሊያስታውቅ ፡ ወደደ ፥ ምሥጢሩም ፡ የክብር ፡ ተስፋ ፡ ያለው ፡ ክርስቶስ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ መሆኑ ፡ ነው ። ፳፰ እኛም ፡ በክርስቶስ ፡ ፍጹም ፡ የሚሆን ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ እናቀርብ ፡ ዘንድ ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ እየገሠጽን ፡ ሰውንም ፡ ሁሉ ፡ በጥበብ ፡ ሁሉ ፡ እያስተማርን ፡ የምንሰብከው ፡ እርሱ ፡ ነው ፤ ፳፱ ለዚህም ፡ ነገር ፡ ደግሞ ፥ በእኔ ፡ በኃይል ፡ እንደሚሠራ ፡ እንደ ፡ አሠራሩ ፡ እየተጋደልሁ ፥ እደክማለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ስለ ፡ እናንተና ፡ በሎዶቅያ ፡ ስላሉት ፡ ፊቴንም ፡ በሥጋ ፡ ስላላዩት ፡ ሁሉ ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ ትልቅ ፡ መጋደል ፡ እንዳለኝ ፡ ልታውቁ ፡ እወዳለሁና ፤ ፪ ልባቸው ፡ እንዲጸናና ፥ በፍቅርም ፡ ተበብረው ፡ በማስተዋል ፡ ወደሚገኝበት ፡ ወደ ፡ መረዳት ፡ ባለ ፡ ጠግነት ፡ ሁሉ ፡ እንዲደርሱ ፥ የእግዚአብሔርንም ፡ ምሥጢር ፡ እርሱንም ፡ ክርስቶስን ፡ እንዲያውቁ ፡ እጋደላለሁ ፤ ፫ የተሰወረ ፡ የጥበብና ፡ የእውቀት ፡ መዝገብ ፡ ሁሉ ፡ በእርሱ ፡ ነውና ። ፬ ማንም ፡ በሚያባብል ፡ ቃል ፡ እንዳያስታችሁ ፡ ይህን ፡ እላለሁ ። ፭ በሥጋ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ብርቅ ፥ በመንፈስ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ነኝና ፥ ሥርዓታችሁንም ፡ በክርስቶስም ፡ ያለውን ፡ የእምነታችሁን ፡ ጽናት ፡ እያየሁ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።

፮ እንግዲህ ፡ ጌታን ፡ ክርስቶስ ፡ ኢየሱስን ፡ እንደ ፡ ተቀበላችሁት ፡ በእርሱ ፡ ተመላለሱ ፤ ፯ ሥር ፡ ሰዳችሁ ፡ በእርሱ ፡ ታንጹ ፥ እንደ ፡ ተማራችሁም ፡ በሃይማኖት ፡ ጽኑ ፥ ምስጋናም ፡ ይብዛላችሁ ።

፰ እንደ ፡ ክርስቶስ ፡ ትምህርት ፡ ሳይሆን ፥ እንደ ፡ ሰው ፡ ወግና ፡ እንደ ፡ ዓለማዊ ፡ እንደ ፡ መጀመሪያ ፡ ትምህርት ፡ ባለ ፡ በፍልስፍና ፡ በከንቱም ፡ መታለል ፡ ማንም ፡ እንዳይማርካችሁ ፡ ተጠበቁ ። ፱ በእርሱ ፡ የመለኮት ፡ ሙላት ፡ ሁሉ ፡ በሰውነት ፡ ተገልጦ ፡ ይኖራልና ፤ ፲ ለአለቅነትና ፡ ለሥልጣንም ፡ ሁሉ ፡ ራስ ፡ በሆነ ፡ በእርሱ ፡ ሆናችሁ ፡ ተሞልታችኋል ። ፲፩ የሥጋንም ፡ ሰውነት ፡ በመገፈፍ ፥ በክርስቶስ ፡ መገረዝ ፥ በእጅ ፡ ባልተደረገ ፡ መገረዝ ፡ በእርሱ ፡ ሆናችሁ ፡ ደግሞ ፡ ተገረዛችሁ ፤ ፲፪ በጥምቀትም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተቀበራችሁ ፥ በጥምቀት ፡ ደግሞ ፥ ከሙታን ፡ በስነሣው ፡ በእግዚአብሔር ፡ አሠራር ፡ በማመናችሁ ፥ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተነሣችሁ ። ፲፫ እናንተም ፡ በበደላችሁና ፡ ሥጋችሁን ፡ ባለመገረዝ ፡ ሙታን ፡ በሆናችሁ ፡ ጊዜ ፥ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሕይወትን ፡ ሰጣችሁ ፤ በደላችሁን ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡ አላችሁ ፤ ፲፬ በእኛ ፡ ላይ ፡ የነበረውን ፡ የሚቃወመንንም ፡ በትእዛዛት ፡ የተጻፈውን ፡ የዕዳ ፡ጽሕፈት ፡ ደመሰሰው ፤ እርሱንም ፡ በመስቀል ፡ ጠርቆ ፡ ከመንገድ ፡ አስወግዶታል ፤ ፲፭ አለቅነትንና ፡ ሥልጣናትን ፡ ገፎ ፥ ድል ፡ በመንሣት ፡ በእርሱ ፡ እያዘራቸው ፡ በግልጥ ፡ አሳያቸው ።

፲፮ እንግዲህ ፡ በመብል ፡ ወይም ፡ በመጠጥ ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ በዓል ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ ወር ፡ መባቻ ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ ሰንበት ፡ ማንም ፡ አይፍረድባችሁ ፤ ፲፯ እነዚህ ፡ ሊመጡ ፡ ያሉት ፡ ነገሮች ፡ ጥላ ፡ ናቸውና ፥ አካሉ ፡ ግን ፡ የክርስቶስ ፡ ነው ። ፲፰ ትሕትናንና ፡ የመላእክትን ፡ አምልኮ ፡ እየወደደ ፥ ባላየውም ፡ ያለ ፡ ፈቃድ ፡ እየገባ ፥ በሥጋዊም ፡ አእምሮ ፡ በከንቱ ፡ እየታበየ ፡ ማንም ፡ አይፍረድባችሁ ፤ ፲፱ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ራስ ፡ ወደሚ

፩ ። ፲፰ ፤ ኤፌ. ፩ ፥ ፳፪ ፤ ራእ. ፩ ፥ ፭ ። ፲፱ ፤ ዮሐ. ፩ ፥ ፲፮ ፤ ኤፌ. ፩ ፥ ፳፫ ። ፳ ፤ ኤፌ. ፩ ፥ ፲ ፤ ፪ ፥ ፲፫ ፤ ፲፬ ፤ ፲፮ ። ፳፩ ፤ ኤፌ. ፪ ፥ ፩ ፤ ፲፪ ፤ ሮሜ ፭ ፥ ፲ ። ፳፪ ፤ ኤፌ. ፭ ፥ ፪ ። ፳፫ ፤ ማር. ፲፮ ፥ ፲፭ ። ፳፬ ፤ ኤፌ. ፫ ፥ ፲፫ ። ፳፭ ፤ ኤፌ. ፫ ፥ ፪ ፤ ፯ ። ፳፮ ፤ ኤፌ. ፫ ፥ ፱ ፤ ሮሜ ፲፮ ፥ ፳፭ ፤ ፳፮ ። ፳፱ ፤ ኤፌ. ፩ ፥ ፲፱ ።

፪ ። ፫ ፤ ፩ ቆሮ. ፩ ፥ ፴ ። ፬ ፤ ኤፌ. ፭ ፥ ፮ ። ፭ ፤ ፩ ቆሮ. ፭ ፥ ፫ ። ፯ ፤ ኤፌ. ፫ ፥ ፲፯ ፤ ፬ ፥ ፲፬ ። ፰ ፤ ገላ. ፬ ፥ ፫ ፤ ፱ ። ፱ ፤ ዮሐ. ፩ ፥ ፲፬ ። ፲ ፤ ኤፌ. ፩ ፥ ፳፩ ፤ ፫ ፥ ፲፱ ። ፲፩ ፤ ሮሜ ፪ ፥ ፳፱ ። ፲፪ ፤ ሮሜ ፮ ፥ ፬ ፤ ፭ ። ፲፫ ፤ ኤፌ. ፪ ፥ ፩ ፤ ፭ ፤ ፲፩ ። ፲፬ ፤ ኤፌ. ፪ ፥ ፲፭ ፤ ፲፮ ። ፲፭ ፤ ዮሐ. ፲፪ ፥ ፴፩ ። ፲፮ ፤ ሮሜ ፲፬ ፥ ፫ ፤ ፭ ። ፲፯ ፤ ዕብ. ፰ ፥ ፭ ፤ ፲ ፥ ፩ ። ፲፱ ፤ ኤፌ. ፬ ፥ ፲፭ ፤ ፲፮ ።

ሆነው ፡ አይጠጋም ፡ ከእርሱም ፡ አካል ፡ ሁሉ ፡ በጅማትና ፡ በማሰሪያ ፡ ምግብን ፡ እየተቀበለ ፡ እየተጋጠመም ፥ እግዚአብሔር ፡ በሚሰጠው ፡ ማደግ ፡ ያድጋል ።

፳፤ ፳፩፤ ከዓለማዊ ፡ ከመጀመሪያ ፡ ትምህርት ፡ ርቃችሁ ፡ ከክርስቶስ ፡ ጋር ፡ ከሞታችሁ ፥ እንደ ፡ ሰው ፡ ሥርዓትና ፡ ትምህርት ፡— አትያዝ ፥ አትቅመስ ፥ አትንካ ፡ ስሚሉት ፡ ትእዛዛት ፡ በዓለም ፡ እንደምትኖሩ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትገዛላችሁ ? እነዚህ ፡ ፳፪፤ ሁሉ ፡ በመደረግ ፡ ሊጠፉ ፡ ተወስነዋልና ። ይህ ፡ እንደ ፡ ገዛ ፡ ፈቃድህ ፡ በማምለክና ፡ በትሕትና ፡ ሥጋንም ፡ በመጨቈን ፡ ጥበብ ፡ ያለው ፡ ይመስላል ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ሥጋ ፡ ያለ ፡ ልክ ፡ እንዳይጠግብ ፡ ለመከልከል ፡ ምንም ፡ አይጠቅምም ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፤ እንግዲህ ፡ ከክርስቶስ ፡ ጋር ፡ ከተነሣችሁ ፥ ክርስቶስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ተቀምጦ ፡ ፪፤ በሰበት ፡ በላይ ፡ ያለውን ፡ እሹ ፤ በላይ ፡ ያለውን ፡ አስቡ ፡ እንጂ ፡ በምድር ፡ ያለውን ፡ አይ ፫፤ ደለም ። ሞታችኋልና ፥ ሕይወታችሁም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ከክርስቶስ ፡ ጋር ፡ ተሰውሮአልና ፤ ፬፤ ሕይወታችሁ ፡ የሆነ ፡ ክርስቶስ ፡ በሚገለጥበት ፡ ጊዜ ፥ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ በክብር ፡ ትገለጣላችሁ ።

፭፤ እንግዲህ ፡ በምድር ፡ ያሉቱን ፡ ብልቶቻችሁን ፡ ግደሉ ፥ እነዚህም ፡ ዝሙትና ፡ ርኵሰት ፡ ፍትወትም ፡ ክፉ ፡ ምኞትም ፡ ጣዖትንም ፡ ማም ፮፤ ለክ ፡ የሆነ ፡ መጐምጀት ፡ ነው ፤ በእነዚህም ፡ ጠንቅ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በማይታዘዙ ፡ ፯፤ ልጆች ፡ ላይ ፡ ይመጣል ፤ እናንተም ፡ ደግሞ ፡ ትኖሩባቸው ፡ በነበራችሁ ፡ ጊዜ ፥ በፊት ፡ በእ ፰፤ ነዚህ ፡ ተመላለሳችሁ ። አሁን ፡ ግን ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ቍጣንና ፡ ንዴትን ፡ ክፋትንም ፥ ከአፋችሁም ፡ ስድብን ፡ የሚያስፍርንም ፡ ንግግር ፡ ፱፤ እነዚህን ፡ ሁሉ ፡ አስወግዱ ፤ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ውሸት ፡ አትነጋገሩ ፥ አሮጌውን ፡ ሰው ፡ ከሥ ፲፤ ራው ፡ ጋር ፡ ገፋችሁታልና ፥ የፈጠረውንም ፡ ምሳሌ ፡ እንዲመስል ፡ እውቀትን ፡ ለማግኘት ፡ የሚታደሰውን ፡ አዲሱን ፡ ሰው ፡ ለብሳችሁታል ፤ ፲፩፤ በዚያም ፡ የግሪክ ፡ ሰው ፡ አይሁዳዊም ፡ የተገረዘም ፡ ያልተገረዘም ፡ አረማዊም ፡ እስኩቴስም ፡ ባሪያም ፡ ጨዋ ፡ ሰውም ፡ መሆን ፡ አልተቻለም ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ክርስቶስ ፡ ሁሉ ፡ ነው ፥ በሁሉም ፡ ነው ።

፲፪፤ እንግዲህ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምርጦች ፡
(፲፩ ፤ እስኩቴስ ፡ ማለት ፡ የወገን ፡ ስም ፡ ነው ።)
ቅዱሳን ፡ ሆናችሁ ፡ የተወደዳችሁም ፡ ሆናችሁ ፥ ምሕረትን ፥ ርኅራኄን ፥ ቸርነትን ፥ ትሕትናን ፥ የዋህነትን ፥ ትዕግሥትን ፡ ልበሱ ፤ ፲፫፤ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ትዕግሥትን ፡ አድርጉ ፥ ማንም ፡ በባልንጀራው ፡ ላይ ፡ የሚነቅፈው ፡ ነገር ፡ ካለው ፥ ይቅር ፡ ተባባሉ ፤ ክርስቶስ ፡ ይቅር ፡ እንዳላችሁ ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ እንዲሁ ፡ አድርጉ ፤ ፲፬፤ በእነዚህም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የፍጻሜ ፡ ማሰሪያ ፡ የሆነ ውን ፡ ፍቅርን ፡ ልበሱት ። ፲፭፤ በአንድ ፡ አካልም ፡ የተጠራችሁለት ፡ ደግሞ ፡ የክርስቶስ ፡ ሰላም ፡ በልባችሁ ፡ ይግዛ ፤ የምታመሰግኑም ፡ ሁኑ ። ፲፮፤ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በሙላት ፡ ይኑርባችሁ ፤ በጥበብ ፡ ሁሉ ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ አስተምሩና ፡ ገሥጹ ፤ በመዝሙርና ፡ በዝማሬ ፡ በመንፈሳዊም ፡ ቅኔ ፡ በጸጋው ፡ በልባችሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዘምሩ ፤ ፲፯፤ እግዚአብሔር ፡ አብን ፡ በእርሱ ፡ እያመሰገናችሁ ፥ በቃል ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ በሥራ ፡ የምታደርጉትን ፡ ሁሉ ፡ በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ ስም ፡ አድርጉት ።

፲፰፤ ሚስቶች ፡ ሆይ ፥ በጌታ ፡ እንደሚገባ ፡ ለባ ፲፱፤ ሎቻችሁ ፡ ተገዙ ። ባሎች ፡ ሆይ ፥ ሚስቶቻችሁን ፡ ውደዱ ፡ መራራም ፡ አትሁኑባቸው ። ፳፤ ልጆች ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡ ለጌታ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ፳፩፤ ነውና ፡ በሁሉ ፡ ለወላጆቻችሁ ፡ ታዘዙ ። አባቶች ፡ ሆይ ፥ ልባቸው ፡ እንዳይዝል ፡ ልጆቻችሁን ፡ አታበሳጩአቸው ። ፳፪፤ ባሪያዎች ፡ ሆይ ፥ በቅን ፡ ልብ ፡ ጌታን ፡ እየፈራችሁ ፡ እንጂ ፥ ሰሰውን ፡ ደስ ፡ እንደምታሰኙ ፡ ለታይታ ፡ የምትገዙ ፡ ሳትሆኑ ፥ በሥጋ ፡ ጌቶቻችሁ ፡ ለሆኑ ፡ በሁሉ ፡ ታዘዙ ። ፳፫፤ ለሰው ፡ ሳይሆን ፡ ለጌታ ፡ እንደምታደርጉ ፥ የምታደርጉትን ፡ ሁሉ ፡ በትጋት ፡ አድርጉት ፥ ፳፬፤ ከጌታ ፡ የርስትን ፡ ብድራት ፡ እንድትቀበሉ ፡ታውቃላችሁና ፤ የምታገለግሉት ፡ ጌታ ፡ ክርስቶስ ፡ ነውና ። ፳፭፤ የሚበድልም ፡ የበደለውን ፡ በብድራት ፡ ይቀበላል ፥ ለሰው ፡ ፊትም ፡ አድልዎ ፡ የለም ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩፤ ጌቶች ፡ ሆይ ፥ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ በሰማይ ፡ ጌታ ፡ እንዳላችሁ ፡ ታውቃላችሁና ፡ ለባሪያዎቻችሁ ፡ በጽድቅና ፡ በቅንነት ፡ አድርጉላቸው ።

፪፤ ከማመስገን ፡ ጋር ፡ በጸሎት ፡ እየነቃችሁ ፡ ስለ ፫፤ እርሱ ፡ ትጉ ፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ የታሰርሁበትን ፡ የክርስቶስን ፡ ምሥጢር ፡ እንድንነግር ፡ እግዚአብሔር ፡ የቃሉን ፡ ደጅ ፡ ይከፍትልን ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ ደግሞ ፡ ጸልዩ ፤ ፬፤ ልናገር ፡ እንደሚገባኝ ፡ ያህል ፡ እገል

፪። ፳፤ ቍ. ፰ ። ፳፩፤ ፩ ጢሞ. ፬ ፥ ፫ ። ፳፪፤ ፩ ቆሮ. ፮ ፥ ፲፫ ፤ ኢሳ. ፳፱ ፥ ፲፫ ።
፫። ፩፤ ዮሐ. ፬ ፥ ፲፬፤ ኤፌ. ፩ ፥ ፳ ። ፬፤ ማቴ. ፳ ፥ ፴፫፤ ፲፯ ፥ ፳፫ ። ፭፤ ፩ ዮሐ. ፫ ፥ ፪ ። ፮፤ ሮሜ. ፰ ፥ ፲፫፤ ኤፌ. ፭ ፥ ፫፤ ኢዮብ ፴፩ ፥ ፳፬ ፤ ፳፰ ። ፯፤ ኤፌ. ፭ ፥ ፮ ። ፰፤ ፱፤ ኤፌ. ፬ ፥ ፳፪ ፤ ፳፭ ፤ ፴፩ ። ፲፤ ዘፍጥ. ፩ ፥ ፳፯፤ ኤፌ. ፬ ፥ ፳፬ ። ፲፩፤ ሮሜ. ፲ ፥ ፲፪፤ ገላ. ፫ ፥ ፳፰ ። ፲፪፤ ፲፫፤ ኤፌ. ፬ ፥ ፪፤ ፴፪፤ ማር. ፲፩ ፥ ፳፭ ። ፲፬፤ ሮሜ. ፲፫ ፥ ፰፤ ፲ ። ፲፭፤ ፊልጵ. ፬ ፥ ፯ ። ፲፮፤ ኤፌ. ፭ ፥ ፲፱ ። ፲፯፤ ፩ ቆሮ. ፲ ፥ ፴፩፤ ኤፌ. ፭ ፥ ፳ ። ፲፰፤ ኤፌ. ፭ ፥ ፳፪ ። ፲፱፤ ኤፌ. ፭ ፥ ፳፭ ። ፳፤ ኤፌ. ፮ ፥ ፩ ። ፳፩፤ ኤፌ. ፮ ፥ ፬ ። ፳፪—፳፭፤ ኤፌ. ፮ ፥ ፭—፰ ። ፳፭፤ ሮሜ. ፪ ፥ ፲፩ ።
፬። ፩፤ ኤፌ. ፮ ፥ ፱ ። ፪—፬፤ ኤፌ. ፮ ፥ ፲፰—፳ ።

ጠው ፡ ዘንድ ፡ ጸልዩልኝ ፡፡

፭ ዘመኑን ፡ እየዋጃችሁ ÷ በውጭ ፡ በሉቱ ፡ ፮ ዘንድ ፡ በጥበብ ፡ ተመላለሱ ፡፡ ለእያንዳንዱ ፡ እን ዴት ፡ እንድትመልሱ ፡ እንደሚገባችሁ ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ ንግግራችሁ ፡ ሁልጊዜ ÷ በጨው ፡ እንደ ፡ ተቀመመ ÷ በጸጋ ፡ ይሁን ፡፡

፯ የተወደደ ፡ ወንድምና ፡ የታመነ ፡ አገልጋይ ፡ በጌታም ፡ አብሮኝ ፡ በሪያ ፡ የሆነ ፡ ቲኪቆስ ፡ ኑሮ ፰፡፱ ዬን ፡ ሁሉ ፡ ያስታውቃችኋል ፤ ወሬያችንን ፡ እንድታውቁና ፡ ልባችሁን ፡ እንዲያጽናና ÷ ከእ ናንተ ፡ ከሆነውና ፡ ከታመነው ፡ ከተወደደውም ፡ ወንድም ፡ ከአናሲሞስ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ የምልከው ፡ ስለዚህ ፡ ምክንያት ፡ ነው ፤ የዚህን ፡ ስፍራ ፡ ወሬ ፡ ሁሉ ፡ ያስታውቁአችኋል ፡፡

፲፡፲፩ ከተገረዙት ፡ ወገን ፡ ያሉት ÷ አብሮ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ የታሰረ ፡ አርስጥሮኮስ ፡ የበርናባስም ፡ የወ ንድሙ ፡ ልጅ ፡ ማርቆስ ፡ ኢዮስጦስም ፡ የተባለ ፡ ኢያሱ ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡላችኋል ፤ ስለ ፡ ማር ቆስ ፡— ወደ ፡ እናንተ ፡ ቢመጣ ÷ ተቀበሉት ፡ የሚል ፡ ትእዛዝ ፡ ተቀበላችሁ ፤ በእግዚአብ ሔር ፡ መንግሥት ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ አብረው ፡ የሚ ሠሩት ፡ እነዚህ ፡ ብቻ ፡ ናቸው ÷ እኔንም ፡ እጽ ናንተውኛል ፡፡ ፲፪ ከእናንተ ፡ የሆነ ፡ የክርስቶስ ፡ ባሪያ ፡ ኤጳፍራ ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርብላችኋል ፤ በእ ግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ሁሉ ፡ ተረድታችሁና ፡ ፍጹማን ፡ ሆናችሁ ፡ እንድትቆሙ ÷ ሁልጊዜ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ በጸሎቱ ፡ ይጋደላል ፡፡ ፲፫ ስለ ፡ እና ንተ ፡ በሎዶቅያም ፡ በኢያራ ፡ ከተማም ፡ ስላ ሉቱ ፡ እጅግ ፡ እንዲቀና ፡ እመሰክርለታለሁና ፡፡ ፲፬ የተወደደው ፡ ባለ ፡ መድኃኒቱ ፡ ሉቃስ ፡ ዴማ ፲፭ ስም ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡላችኋል ፡፡ በሎዶቅያ ፡ ላሉቱ ፡ ወንድሞችና ፡ ለንምፉን ፡ በቤቱም ፡ ላለች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልን ፡፡ ፲፮ ይህችም ፡ መልእክት ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ከተነ በበች ፡ በኋላ ÷ በሎዶቅያ ፡ ሰዎች ፡ ማኅበር ፡ ደግሞ ፡ እንድትነበብ ፡ አድርጉ ፤ ከሎዶቅያም ፡ የምትገኘውን ፡ መልእክት ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ አንብቡ ፡፡ ፲፯ ለአክሪጳም ፡— በጌታ ፡ የተቀበልኸ ውን ፡ አገልግሎት ፡ እንድትፈጽመው ፡ ተጠን ቀቅ ፡ በሉልኝ ፡፡

፲፰ በገዛ ፡ እጄ ፡ የተጻፈ ፡ የእኔ ፡ የጳውሎስ ፡ ሰላ ምታ ፡ ይህ ፡ ነው ፡፡ እስራቴን ፡ አስቡ ፡፡ ጸጋ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፡፡

# መጀመሪያይቱ ፡ የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ተሰሎንቄ ፡ ሰዎች ፡፡

ምዕራፍ ፡ ፩ ፡፡

፩ ጳውሎስና ፡ ስልዋኖስ ፡ ጢሞቴዎስም ÷ በእ ግዚአብሔር ፡ አብ ፡ በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶ ስም ፡ ወደምትሆን ፡ ወደ ፡ ተሰሎንቄ ፡ ሰዎች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፤

ከእግዚአብሔር ፡ ከአባታችን ፡ ከጌታ ፡ ከኢ የሱስ ፡ ክርስቶስም ፡ ጸጋ ፡ ሰላምም ፡ ለእናንተ ፡ ይሁን ፡፡

፪፡፫ በጸሎታችን ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ስናሳ ስብ ÷ የእምነታችሁን ፡ ሥራ ፡ የፍቅራችሁንም ፡ ድካም ፡ በጌታችንም ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ያለውን ፡ የተስፋችሁን ፡ መጽናት ፡ በአምላካች ንና ፡ በአባታችን ፡ ፊት ፡ ሳናቋርጥ ፡ እያሰብን ÷ እግዚአብሔርን ፡ ሁልጊዜ ፡ በሁላችሁ ፡ ምክን ፬ ያት ፡ እናመሰግናለን ፤ በእግዚአብሔር ፡ የምት ወደዱ ፡ ወንድሞች ፡ ሆይ ÷ እንደ ፡ ተመረጣ ፭ ችሁ ፡ እውቀናልና ፡፡ ወንጌላችን ፡ በኃይልና ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በብዙ ፡ መረዳትም ፡ እንጂ ፡ በቃል ፡ ብቻ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ አልመጣምና ፤ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ፮ ነበርን ፡ ታውቃላችሁ ፡፡ ደግሞ ፡ እናንተ ፡ ቃሉን ፡ በብዙ ፡ መከራ ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ደስታ ፡ ጋር ፡ ተቀብላችሁ ÷ እኛንና ፡ ጌታን ፡ ፯ የምትመስሉ ፡ ሆናችሁ ፤ ስለዚህም ፡ በመቄዶ ንያና ፡ በአካይያ ፡ ላሉት ፡ ምእመናን ፡ ሁሉ ፡ ፰ ምሳሌ ፡ ሆናችሁላቸው ፡፡ ከእናንተ ፡ ወጥቶ ፡ የጌታ ፡ ቃል ፡ በመቄዶንያና ፡ በአካይያ ፡ ብቻ ፡ አልተሰማምና ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ምንም ፡ እንድንና ገር ፡ እስከማያስፈልግ ፡ ድረስ ÷ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የሚሆን ፡ እምነታችሁ ፡ በሁሉ ፡ ስፍራ ፡ ፱፡፲ ተወርቶአል ፡፡ እነርሱ ፡ ራሳቸው ፡ ወደ ፡ እና ንተ ፡ መግባታችን ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ ይናገራሉና ፤ ለሕያውና ፡ ለእውነተኛ ፡ አምላክም ፡ ታገለግሉ ፡ ዘንድ ÷ ከሙታንም ፡ ያስነሣውን ፡ ልጁን ፡ እርሱንም ፡ ኢየሱስን ፡ ከሚመጣው ፡ ቍጣ ፡ የሚያድነንን ፡ ከሰማይ ፡ ትጠብቁ ፡ ዘንድ ÷ ከጣዖቶች ፡ ወደ ፡ እግዚአብ ሔር ፡ እንዴት ፡ ዘወር ፡ እንዳላችሁ ፡ ይናገራሉ ፡፡

ምዕራፍ ፡ ፪ ፡፡

፩ ወንድሞች ፡ ሆይ ÷ ራሳችሁ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ መግባታችን ፡ ከንቱ ፡ እንዳልሆነ ፡ ታውቃላች ፪ ሁና ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ እንደምታውቁት ፡ በፊልጵ

፩። ፩ ፤ ኤፌ. ፭ ÷ ፲፭ ፣ ፲፮ ፡፡ ፮ ፤ ማር. ፱ ÷ ፶ ፤ ፩ ጴጥ. ፫ ÷ ፲፭ ፡፡ ፯ ፡ ፰ ፤ ኤፌ. ፮ ÷ ፳፩ ፡ ፳፪ ፡፡ ፱ ፤ ፊልሞ. ፲ ፡፡ ፲ ፤ የሐዋ. ፳፯ ÷ ፪ ፤ ፲፪ ÷ ፲፪ ፤ ፲፭ ÷ ፴፯ ፣ ፴፱ ፡፡ ፲፪ ፤ ምዕ. ፩ ÷ ፯ ፡፡ ፲፬ ፤ የሐዋ. ፲፯ ÷ ፲ ፡፡ ፲፯ ፤ ፊልሞ. ፪ ፡፡

፩። ፩ ፤ የሐዋ. ፲፭ ÷ ፳፪ ፣ ፵ ፤ ፲፯ ÷ ፩—፫ ፤ ፲፯ ÷ ፩ ፤ ፪ ተሰ. ፩ ÷ ፩ ። ፫ ፤ ፪ ተሰ. ፩ ÷ ፫ ፣ ፱ ፡፡ ፬ ፤ ፪ ተሰ. ፪ ÷ ፲፫ ፣ ፲፬ ፡፡ ፭ ፤ ፩ ቆሮ. ፪ ÷ ፬ ፡፡ ፯ ፤ ፩ ቆሮ. ፲፩ ÷ ፩ ፤ የሐዋ. ፲፯ ÷ ፩—፲ ፡፡ ፲ ፤ የሐዋ. ፩ ÷ ፲፩ ፤ ማቴ. ፫ ፡ ፯ ፡፡

፪። ፪ ፤ የሐዋ. ፲፯ ÷ ፳፪—፳፬ ፤ ፲፯ ÷ ፩—፱ ፡፡

ጠው ፡ ዘንድ ፡ ጸልዩልኝ ።

፭ ዘመኑን ፡ እየዋጃችሁ ፥ በውጭ ፡ ባሉቱ ፡ ፮ ዘንድ ፡ በጥበብ ፡ ተመላለሱ ። ለእያንዳንዱ ፡ እን ዴት ፡ እንድትመልሱ ፡ እንደሚገባችሁ ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ ንግግራችሁ ፡ ሁልጊዜ ፥ በጨው ፡ እንደ ፡ ተቀመመ ፥ በጸጋ ፡ ይሁን ።

፯ የተወደደ ፡ ወንድምና ፡ የታመነ ፡ አገልጋይ ፡ በጌታም ፡ እብሮኝ ፡ ባሪያ ፡ የሆነ ፡ ቲኪቆስ ፡ ኑሮ ፰፡፱ ዬን ፡ ሁሉ ፡ ያስታውቃችኋል ፤ ወሬያችንን ፡ እንድታውቁና ፡ ልባችሁን ፡ እንዲያጽናና ፥ ከእ ናንተ ፡ ከሆነውና ፡ ከታመነው ፡ ከተወደደውም ፡ ወንድም ፡ ከአናሲሞስ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ የምልከው ፡ በስለዚሁ ፡ ምክንያት ፡ ነው ፤ የዚህን ፡ በፍራ ፡ ወሬ ፡ ሁሉ ፡ ያስታውቁአችኋል ።

፲፡፲፩ ከተገረዙት ፡ ወገን ፡ ያሉት ፥ አብሮ ፥ ከእኔ ፡ ጋር ፡ የታሰረ ፡ አርስጥሮኮስ ፡ የበርናባስም ፡ የወ ንድሙ ፡ ልጅ ፡ ማርቆስ ፡ ኢዮስጦስም ፡ የተባለ ፡ ኢያሱ ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡላችኋል ፤ ስለ ፡ ማር ቆስ ፦ ወደ ፡ እናንተ ፡ ቢመጣ ፥ ተቀበሉት ፡ የሚል ፡ ትእዛዝ ፡ ተቀበላችሁ ፤ በእግዚአብ ሔር ፡ መንግሥት ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ አብረው ፡ የሚ ሠሩት ፡ እነዚህ ፡ ብቻ ፡ ናቸው ፥ እኔንም ፡ አጽ ናንተውኛል ። ከእናንተ ፡ የሆነ ፡ የክርስቶስ ፡ ፲፪ ባሪያ ፡ ኤጳፍራ ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርብላችኋል ፤ በእ ግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ሁሉ ፡ ተረድታችሁና ፡ ፍጹማን ፡ ሆናችሁ ፡ እንድትቆሙ ፥ ሁልጊዜ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ በጸሎቱ ፡ ይጋደላል ። ስለ ፡ እና ፲፫ ንተ ፡ በሎዶቅያም ፡ በኢያራ ፡ ከተማም ፡ ስላ ሉቱ ፡ እጅግ ፡ እንዲቀና ፡ እመሰክርለታለሁና ።

፲፬ የተወደደው ፡ ባለ ፡ መድኃኒቱ ፡ ሉቃስ ፡ ዴማ ስም ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡላችኋል ። በሎዶቅያ ፡ ፲፭ ላሉቱ ፡ ወንድሞችና ፡ ለንምፋን ፡ በቤቱም ፡ ላለች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሰላምታ ፡ አቅርቡልን ። ፲፮ ይህችም ፡ መልእክት ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ከተነ በበች ፡ በኋላ ፥ በሎዶቅያ ፡ ሰዎች ፡ ማኅበር ፡ ደግሞ ፡ እንድትነበብ ፡ አድርጉ ፤ ከሎዶቅያም ፡ የምትገኘውን ፡ መልእክት ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ ፲፯ አንብቡ ። ለአክረጳም ፦ በጌታ ፡ የተቀበልኸ ውን ፡ አገልግሎት ፡ እንድትፈጽመው ፡ ተጠን ቀቅ ፡ በሉልኝ ።

፲፰ በገዛ ፡ እጄ ፡ የተጻፈ ፡ የእኔ ፡ የጳውሎስ ፡ ሰላ ምታ ፡ ይህ ፡ ነው ። እስራቴን ፡ አስቡ ። ጸጋ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይሁን ።

# መጀመሪያይቱ ፡ የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ተሰሎንቄ ፡ ሰዎች ።

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ ጳውሎስና ፡ ስልዋኖስ ፡ ጢሞቴዎስም ፥ በእ ግዚአብሔር ፡ አብ ፡ በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶ ስም ፡ ወደምትሆን ፡ ወደ ፡ ተሰሎንቄ ፡ ሰዎች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፤

ከእግዚአብሔር ፡ ከአባታችን ፡ ከጌታ ፡ ከኢ የሱስ ፡ ክርስቶስም ፡ ጸጋ ፡ ሰላምም ፡ ለእናንተ ፡ ይሁን ።

፪፡፫ በጸሎታችን ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ በናሳ ስብ ፥ የእምነታችሁን ፡ ሥራ ፡ የፍቅራችሁንም ፡ ድካም ፡ በጌታችንም ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ያለውን ፡ የተስፋችሁን ፡ መጽናት ፡ በአምላካች ንና ፡ በአባታችን ፡ ፊት ፡ ሳናቋርጥ ፡ እያሰብን ፥ እግዚአብሔርን ፡ ሁልጊዜ ፡ በሁላችሁ ፡ ምክን ፬ ያት ፡ እናመሰግናለን ፤ በእግዚአብሔር ፡ የምት ወደዱ ፡ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ እንደ ፡ ተመረጣ ፭ ችሁ ፡ እውቀናልና ። ወንጌላችን ፡ በኃይልና ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በብዙ ፡ መረዳትም ፡ እንጂ ፡ በቃል ፡ ብቻ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ አልመጣምና ፤ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ፮ ነበርን ፡ ታውቃላችሁ ። ደግሞ ፡ እናንተ ፡ ቃሉን ፡ በብዙ ፡ መከራ ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ደስታ ፡ ጋር ፡ ተቀብላችሁ ፥ እኛንና ፡ ጌታን ፡ ፯ የምትመስሉ ፡ ሆናችሁ ፤ ስለዚህም ፡ በመቄዶ ንያና ፡ በአካይያ ፡ ላሉት ፡ ምእመናን ፡ ሁሉ ፡ ፰ ምሳሌ ፡ ሆናችሁላቸው ። ከእናንተ ፡ ወጥቶ ፡ የጌታ ፡ ቃል ፡ በመቄዶንያና ፡ በአካይያ ፡ ብቻ ፡ አልተሰማምና ፥ ነገር ፡ ግን ፡ ምንም ፡ እንድንና ገር ፡ እስከማያስፈልግ ፡ ድረስ ፥ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የሚሆን ፡ እምነታችሁ ፡ በሁሉ ፡ ስፍራ ፡ ፱፡፲ ተወርቶአል ። እነርሱ ፡ ራሳቸው ፡ ወደ ፡ እና ንተ ፡ መግባታችን ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ ይናገራሉና ፤ ለሕያውና ፡ ለእውነተኛ ፡ አምላክም ፡ ታገለግሉ ፡ ዘንድ ፥ ከሙታንም ፡ ያስነሣውን ፡ ልጁን ፡ እርሱንም ፡ ኢየሱስን ፡ ከሚመጣው ፡ ቍጣ ፡ የሚያድነንን ፡ ከሰማይ ፡ ትጠብቁ ፡ ዘንድ ፥ ከጣዖቶች ፡ ወደ ፡ እግዚአብ ሔር ፡ እንዴት ፡ ዘወር ፡ እንዳላችሁ ፡ ይናገራሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ራሳችሁ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ መግባታችን ፡ ከንቱ ፡ እንዳልሆነ ፡ ታውቃላች ፪ ሁና ። ነገር ፡ ግን ፡ እንደምታውቁት ፡ በፊልጵ

፱ ። ፭ ፤ ኤፌ ፡ ፭ ፥ ፲፭ ፡ ፲፯ ። ፮ ፤ ማር ፡ ፱ ፥ ፶ ፤ ፩ ጴጥ ፡ ፫ ፥ ፲፭ ። ፯ ፡ ፰ ፤ ኤፌ ፡ ፮ ፥ ፳፩ ፡ ፳፪ ። ፱ ፤ ፊልሞ ፡ ፲ ። ፲ ፤ የሐዋ ፡ ፳፯ ፥ ፪ ፤ ፲፪ ፡ ፳፭ ፤ ፲፭ ፥ ፴፯ ፡ ፴፱ ። ፲፪ ፤ ም ፡ ፩ ፥ ፯ ። ፲፬ ፤ የሐዋ ፡ ፲፮ ፥ ፲ ። ፲፯ ፤ ፊልሞ ፡ ፪ ።

፩ ። ፩ ፤ የሐዋ ፡ ፲፭ ፥ ፳፪ ፡ ፵ ፤ ፲፯ ፥ ፩—፫ ፤ ፲፯ ፥ ፭ ፤ ፪ ተሰ ፡ ፩ ፥ ፩ ። ፫ ፤ ፪ ተሰ ፡ ፩ ፥ ፫ ፡ ፬ ። ፬ ፤ ፪ ተሰ ፡ ፪ ፥ ፲፫ ፡ ፲፱ ። ፭ ፤ ፩ ቆሮ ፡ ፪ ፥ ፬ ። ፮ ፤ ፩ ቆሮ ፡ ፲፩ ፥ ፩ ፤ የሐዋ ፡ ፲፯ ፥ ፭—፲ ። ፲ ፤ የሐዋ ፡ ፩ ፥ ፲፩ ፤ ማቴ ፡ ፫ ፥ ፯ ።

፪ ። ፪ ፤ የሐዋ ፡ ፲፮ ፥ ፳፪—፳፬ ፤ ፲፯ ፥ ፪—፱ ።

ስዩስ፡ አስቀድመን፡ መከራ፡ ተቀብለን፡ ተንገ ሳትቀንም ፥ በብዙ፡ ገድል፡ የእግዚአብሔርን፡ ወንጌል፡ ለእናንተ፡ እንናገር፡ ዘንድ፡ በአምላክ
፫፤ ችን፡ ደፈርን ። ልመናችን፡ ከስሕተት፡ ወይም፡ ከርኵሰት፡ ወይም፡ ከተንኰል፡ አልነበረምና ፤
፬፤ ነገር፡ ግን፡ ወንጌልን፡ አደራ፡ ይሰጠን፡ ዘንድ፡ እግዚአብሔር፡ የታመንን፡ ሆነን፡ እንዳገኘን፡ መጠን ፥ እንዲሁ፡ እንናገራለን ፥ ልባችንን፡ የሚመረምር፡ እግዚአብሔርን፡ እንጂ፡ ሰውን፡
፭፤ ደስ፡ እንደምናሰኝ፡ አይደለም ። እንደምታ ውቁ ፥ አያቈላመጥን፡ ሕኖ፡ አልተናገርንም ፥ እግዚአብሔርም፡ እንደሚመሰክር፡ አያመክ
፮፤ ኘን፡ በመጐምጀት፡ አልሠራንም ፤ የክርስቶ ስም፡ ሐዋርያት፡ እንደ፡ መሆናችን፡ ልንከብ ድባችሁ፡ ስንችል ፥ ከእናንተ፡ ቢሆን፡ ወይም፡ ከሌሎች፡ ክብርን፡ ከሰው፡ አልፈለግንም ።
፯፤ ነገር፡ ግን፡ ሞግዚት፡ የራስዋን፡ ልጆች፡ እንደ ምትከበክብ ፥ በመካከላችሁ፡ የዋሆች፡ ሆንን ፤
፰፤ እንዲሁም፡ አያፈቀርናችሁ፡ የእግዚአብሔርን፡ ወንጌል፡ ለማካፈል፡ ብቻ፡ ሳይሆን፡ የገዛ፡ ነፍ ሳችንን፡ ደግሞ፡ እናካፍላችሁ፡ ዘንድ፡ በጎ፡ ፈቃዳችን፡ ነበረ ፥ ለእኛ፡ የተወደዳችሁ፡ ሆና ችሁ፡ ነበርና ።
፱፤ ወንድሞች፡ ሆይ ፥ ድካማችንና፡ ጥረታችን፡ ትዝ፡ ይላችኋልና ፤ ከእናንተ፡ በአንዱ፡ ስንኳ፡ እንዳንከብድበት፡ ሌሊትና፡ ቀን፡ እየሠራን ፥ የእግዚአብሔርን፡ ወንጌል፡ ለእናንተ፡ ሰበክን ።
፲፤ በእናንተ፡ በምታምኑ፡ ዘንድ፡ በእንዴት፡ ያለ፡ ቅድስናና፡ ጽድቅ፡ ነቀፋም፡ በሌለበት፡ ኑሮ፡ እንደ፡ ኄድን ፥ እናንተና፡ እግዚአብሔር፡ ምስ
፲፩፡፲፪፤ ክሮች፡ ናችሁ ፤ ወደ፡ መንግሥቱ፡ ወደ፡ ክብ ሩም፡ ለጠራችሁ፡ ለእግዚአብሔር፡ እንደሚ ገባ፡ ትመላለሱ፡ ዘንድ፡ እየመከርንና፡ እያጽ ናን፡ እየመሰከርንላችሁም ፥ አባት፡ ለልጆቹ፡ እንደሚሆን፡ ለእያንዳንዳችሁ፡ እንደ፡ ሆንን፡ ታውቃላችሁና ።
፲፫፤ ስለዚህም፡ የመልእክትን፡ ቃል፡ እርሱም፡ የእግዚአብሔር፡ ቃል፡ ከእኛ፡ በተቀበላችሁ፡ ጊዜ ፥ በእውነት፡ እንዳለ፡ በእናንተ፡ በምታ ምኑ፡ ደግሞ፡ እንደሚሠራ፡ እንደ፡ እግዚአብ ሔር፡ ቃል፡ እንጂ፡ እንደ፡ ሰው፡ ቃል፡ አድ ርጋችሁ፡ ስላልተቀበላችሁት ፥ እኛ፡ ደግሞ፡ እግዚአብሔርን፡ ሳናቋርጥ፡ እናመሰግናለን ።
፲፬፤ እናንተ ፥ ወንድሞች፡ ሆይ ፥ በይሁዳ፡ የሚኖ ሩትን፡ በክርስቶስ፡ ኢየሱስ፡ ያሉትን፡ የእግ ዚአብሔርን፡ ማኅበሮች፡ የምትመስሉ፡ ሆና ችኋልና ፤ እነርሱ፡ ከአይሁድ፡ መከራ፡ እንደ፡ ተቀበሉ ፥ እናንተ፡ ደግሞ፡ ያንን፡ መከራ፡
፲፭፤ ከአገራችሁ፡ ሰዎች፡ ተቀብላችኋልና ። እነዚ ያም፡ ጌታን፡ ኢየሱስን፡ ደግሞ፡ ገደሉ፡ ነቢያ ትንም፡ እኛንም፡ አሳደዱ ፥ እግዚአብሔርንም፡ ደስ፡ አያሰኙም ፥ ሰዎችንም፡ ሁሉ፡ ይቃወ
፲፮፤ ማሉ ፥ ሁልጊዜ፡ ኃጢአታቸውን፡ ይፈጽሙ፡ ዘንድ፡ አሕዛብ፡ እንዲድኑ፡ እንዳንናገራቸው፡ ይከለክሉናልና ። ነገር፡ ግን፡ ቍጣው፡ ወደ፡ እነርሱ፡ ፈጽሞ፡ ደርሶአል ።
፲፯፤ እኛ፡ ግን ፥ ወንድሞች፡ ሆይ ፥ በልብ፡ ያይ ደለ፡ ፊት፡ ለፊት፡ ለጥቂት፡ ጊዜ፡ እጥተናችሁ ፥ በብዙ፡ ናፍቆት፡ ፊታችሁን፡ ለማየት፡ እጅግ፡
፲፰፤ ሞከርን ፤ ወደ፡ እናንተ፡ ልንመጣ፡ ወደን፡ ነበርና ፥ እኔ፡ ጳውሎስም፡ አንድና፡ ሁለት፡
፲፱፤ ጊዜ ፥ ሰይጣን፡ ግን፡ አዘገየን ። ተስፋችን፡ ወይስ፡ ደስታችን፡ ወይስ፡ የትምክህታችን፡ አክሊል፡ ማን፡ ነው ? በጌታችን፡ በኢየሱስ፡ ፊት፡ በመምጣቱ፡ እናንተ፡ አይደላችሁምን ?
፳፤ እናንተ፡ ክብራችን፡ ደስታችንም፡ ናችሁና ።

## ምዕራፍ፡ ፫ ።

፩፤ ስለዚህ፡ ወደ፡ ፊት፡ እንታገሥ፡ ዘንድ፡ በል ተቻለን፡ ጊዜ ፥ በአቴና፡ ብቻችንን፡ ልንቀር፡
፪፤ በጎ፡ ፈቃዳችን፡ ሆነ ። ስለ፡ እምነታችሁም፡ እንዲያጸናችሁና፡ እንዲመክራችሁ፡ ወንድማ ችንን፡ የእግዚአብሔርንም፡ አገልጋይ፡ ከእኛ፡ ጋርም፡ አብሮ፡ በክርስቶስ፡ ወንጌል፡ የሚሠ
፫፤ ራውን፡ ጢሞቴዎስን፡ ላክነው ፤ በዚህ፡ መከራ፡ ማንም፡ እንዳይናወጥ ፥ ለዚህ፡ እንደ፡ ተመረ
፬፤ ጥን፡ ራሳችሁ፡ ታውቃላችሁና ። በእውነት፡ ከእናንተ፡ ጋር፡ ሳለን ፥ መከራ፡ እንቀበል፡ ዘንድ፡ እንዳለን፡ አስቀድመን፡ እንነግራችሁ፡ ነበር ፤ እንዲሁም፡ ደግሞ፡ ሆነ ፥ ይህንም፡
፭፤ ታውቃላችሁ ። ስለዚህ፡ እኔ፡ ደግሞ፡ ወደ፡ ፊት፡ እታገሥ፡ ዘንድ፡ በልተቻለኝ፡ ጊዜ፡— ፈታኙ፡ ምናልባት፡ ፈትኖአችዋል፡ ድካማች ንም፡ ከንቱ፡ ሆኖአል፡ ብዬ፡ እምነታችሁን፡ ለማወቅ፡ ላክሁ ።
፮፤ አሁን፡ ግን፡ ጢሞቴዎስ፡ ከእናንተ፡ ዘንድ፡ ወደ፡ እኛ፡ መጥቶ፡ ስለ፡ እምነታችሁና፡ ስለ፡ ፍቅራችሁ፡ የምስራች፡ ብሎ፡ በነገረን፡ ጊዜ ፥ እኛም፡ አናያችሁ፡ ዘንድ፡ እንደምንናፍቅ፡ ታዩን፡ ዘንድ፡ እየናፈቃችሁ፡ ሁልጊዜ፡ በመ
፯፤ ልካም፡ እንደምታስቡን፡ በነገረን፡ ጊዜ ፥ ስለ ዚህ ፥ ወንድሞች፡ ሆይ ፥ በእምነታችሁ፡ በኩል፡ በችግራችንና፡ በመከራችን፡ ሁሉ፡ ስለ፡ እና
፰፤ ንተ፡ ተጽናናን ፤ እናንተ፡ በጌታ፡ ጸንታችሁ፡ ብትቆሙ ፥ አሁን፡ በሕይወት፡ እንኖራለንና ።
፱፡፲፤ ፊታችሁን፡ ልናይ፡ በእምነታችሁም፡ የጐደለ ውን፡ ልንሞላበት፡ ሌሊትና፡ ቀን፡ ከመጠን፡ ይልቅ፡ እየጸለይን ፥ በአምላካችን፡ ፊት፡ ከእና

፪። ፫፤ ፪ ቆሮ. ፬፥፪። ፬፤ ፩ ጢሞ. ፩፥፲፩። ፭፤ ፪ ተሰ. ፫፥፰። ፮፤ የሐዋ. ፳፥፫። ፲፪፤ ኤፌ. ፬፥፩፤ ፩ ጴጥ. ፩፥፲። ፲፫፤ ማቴ. ፲፥፵፤ ገላ. ፬፥፲፬። ፲፬፤ ፪ ተሰ. ፩፥፬፤ ፩። ፲፭፡፲፮፤ ማቴ. ፳፫፥፴፪—፴፯፤ ሉቃ. ፳፬፥ ፳። ፲፱፤ ፪ ቆሮ. ፩፥፲፬፤ ፊልጵ. ፪፥፲፮።
፫። ፩፤ የሐዋ. ፲፯፥፲፭፡፲፭። ፪፤ ፩ ጢሞ. ፩፥፪። ፫፤ ፪ ጢሞ. ፫፥፲፪። ፭፤ ፊልጵ. ፪፥፲፱። ፮፤ የሐዋ. ፲፰፥ ፭። ፯፤ ፪ ቆሮ. ፩፥፬። ፲፤ ፪ ቆሮ. ፲፫፥፱።

ንተ ፡ የተነሣ ፡ ስለምንደሰተው ፡ ደስታ ፡ ሁሉ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ በእናንተ ፡ ምክንያት ፡ ምን ፡
ያህል ፡ ምስጋና ፡ እናስረክብ ፡ ዘንድ ፡ እንችላ
ለን ?

፲፩፤ እምላካችንና ፡ አበታችን ፡ ራሱ ፡ ጌታችንም ፡
ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ መንገዳችንን ፡
፲፪፡፲፫፡ ያቅና ፤ ጌታችንም ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ከቅዱ
ሳኑ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ሲመጣ ÷ በአምላካችንና ፡ በአበ
ታችን ፡ ፊት ፡ በቅድስና ፡ ነቀፋ ፡ የሌለበት ፡ አድ
ርጎ ፡ ልባችሁን ፡ ያጸና ፡ ዘንድ ÷ እኛ ፡ ደግሞ ፡
ለእናንተ ፡ እንደምንሆን ፡ ጌታ ፡ እርስ ፡ በእርሳ
ችሁ ፡ ያላችሁን ፡ ለሁሉም ፡ የሚሆን ፡ ፍቅራ
ችሁን ፡ ያብዛ ፡ ይጨምርም ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩፤ እንግዲህ ፡ በቀረውስ ÷ ወንድሞች ፡ ሆይ ÷
ልትመላለሱ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ደስ ፡ ልታ
ሰኙ ፡ እንዴት ፡ እንደሚገባችሁ ፡ ከእኛ ፡ ዘንድ ፡
እንደ ፡ ተቀበላችሁ ÷ እናንተ ፡ ደግሞ ፡ እንደም
ትመላለሱ ÷ ከፊት ፡ ይልቅ ፡ ትበዙ ፡ ዘንድ ፡
በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ እንለምናችኋለን ፡ እንመክ
፪፤ ራችሁማለን ። በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ የትኛውን ፡
ትእዛዝ ፡ እንደ ፡ ሰጠናችሁ ፡ ታውቃላችሁና ።
፫፤ ይህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ እርሱም ፡ መቀ
፬፡፭፡ ደሳችሁ ፡ ነውና ፤ ከዝሙት ፡ እንድትርቁ ÷ እግ
ዚአብሔርን ፡ እንደማያውቁ ፡ አሕዛብ ፡ በፍት
ወት ፡ ምኞት ፡ አይደለም ፡ እንጂ ÷ ከእናንተ ፡
እያንዳንዱ ፡ የራሱን ፡ ዕቃ ፡ በቅድስናና ፡ በክ
፮፤ ብር ፡ ያገኝ ፡ ዘንድ ፡ እንዲያውቅ ፤ አስቀድመን ፡
ደግሞ ፡ እንዳልናችሁና ፡ እንደ ፡ መሰከርንላ
ችሁ ÷ ጌታ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ የሚበቀል ፡
ነውና ፡ ማንም ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ አይተላለፍ ፡ ወን
፯፤ ድሙንም ፡ አያታልል ። ለርኵሰት ፡ ሳይሆን ፡
፰፤ እግዚአብሔር ፡ በቅድስና ፡ ጠርቶናልና ። እን
ግዲህ ፡ የሚጥል ፡ ሰውን ፡ የጣለ ፡ አይደለም ÷
መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ በእናንተ ፡ እንዲኖር ፡ የሰ
ጠውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ነው ፡ እንጂ ።
፱፤ እናንተ ፡ ራሳችሁ ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ልት
ዋደዱ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተምራችኋልና ፡ ስለ ፡
ወንድማማች ፡ መዋደድ ፡ ማንም ፡ ይጽፍላችሁ ፡
፲፡፲፩፡፲፪ ዘንድ ፡ አያስፈልጋችሁም ፤ እንዲሁ ፡ በመቄ
ዶንያ ፡ ሁሉ ፡ ላሉት ፡ ወንድሞች ፡ ሁሉ ፡ ታደ
ርጋላችሁና ። ነገር ፡ ግን ÷ ወንድሞች ፡ ሆይ ÷
ከፊት ፡ ይልቅ ፡ ልትበዙ ÷ በጸጥታም ፡ ትኖሩ ፡
ዘንድ ፡ ልትቀኑ ÷ የራሳችሁንም ፡ ጉዳይ ፡ ልትጠ
ነቀቁ ÷ እንዳዘዝናችሁም ÷ በውጭ ፡ በሉት ፡
ዘንድ ፡ በአገብብ ፡ እንድትመላለሱ ÷ አንዳችም ፡
እንዳያስፈልጋችሁ ፡ በእጃችሁ ፡ ልትሠሩ ፡ እን
ለምናችኋለን ።

፲፫፤ ነገር ፡ ግን ÷ ወንድሞች ፡ ሆይ ÷ ተስፋ ፡ እን
ደሌላቸው ፡ እንደ ፡ ሌሎች ፡ ደግሞ ፡ እንዳታ
ዝኑ ÷ እንቀላፍተው ፡ ስላሉቱ ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡
፲፬፤ እንወዳለን ። ኢየሱስ ፡ እንደ ፡ ሞተና ፡ እንደ ፡
ተነሣ ፡ ከመንን ÷ እንዲሁም ፡ በኢየሱስ ፡ ያንቀላ
ፉቱን ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ያመጣቸ
፲፭፤ ዋልና ። በጌታ ፡ ቃል ፡ የምንላችሁ ፡ ይህ ፡
ነውና ፤ እኛ ፡ ሕያዋን ፡ ሆነን ፡ ጌታ ፡ እስኪመጣ ፡
ድረስ ፡ የምንቀር ፡ ያንቀላፉቱን ፡ እንቀድምም ፤
፲፮፤ ጌታ ፡ ራሱ ፡ በትእዛዝ ፡ በመላእክትም ፡ አለቃ ፡
ድምፅ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ መለከት ፡ ከሰማይ ፡
ይወርዳልና ÷ በክርስቶስም ፡ የሞቱ ፡ አስቀድ
፲፯፤ መው ፡ ይነሣሉ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እኛ ፡ ሕያ
ዋን ፡ ሆነን ፡ የምንቀረው ÷ ጌታን ፡ በአየር ፡ ለመ
ቀበል ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ በደመና ፡ እንነጠቃለን ፤
እንዲሁም ፡ ሁልጊዜ ፡ ከጌታ ፡ ጋር ፡ እንሆናለን ።
፲፰፤ ስለዚህ ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ በዚህ ፡ ቃል ፡ ተጽ
ናኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩፤ ወንድሞች ፡ ሆይ ÷ ስለ ፡ ዘመናትና ፡ ስለ ፡
ወራት ፡ ምንም ፡ እንዲጻፍላችሁ ፡ አያስፈልጋች
፪፤ ሁም ፤ የጌታ ፡ ቀን ፡ ሌባ ፡ በሌሊት ፡ እንደሚ
መጣ ÷ እንዲሁ ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ ራሳችሁ ፡ አጥ
፫፤ ብቃችሁ ፡ አውቃችኋልና ። ሰላምና ፡ ደኅንነት ፡
ነው ፡ ሲሉ ÷ ያን ፡ ጊዜ ፡ ምጥ ፡ እርጉዝን ፡ እንደ
ሚይዛት ፡ ጥፋት ፡ በድንገት ፡ ይመጣባቸዋል ፡
፬፤ ከቶም ፡ አያመልጡም ። እናንተ ፡ ግን ÷ ወንድ
ሞች ፡ ሆይ ÷ ቀኑ ፡ እንደ ፡ ሌባ ፡ ይደርስባችሁ ፡
፭፤ ዘንድ ፡ በጨለማ ፡ አይደላችሁም ÷ ሁላችሁ ፡
የብርሃን ፡ ልጆች ፡ የቀንም ፡ ልጆች ፡ ናችሁና ።
እኛ ፡ ከሌሊት ፡ ወይም ፡ ከጨለማ ፡ አይደለ
፮፤ ንም ፤ እንግዲያስ ፡ እንንቃ ፡ በመጠንም ፡ እን
፯፤ ኑር ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ ሌሎች ፡ አናንቀላፋ ። የሚ
ያንቀላፉ ፡ በሌሊት ፡ ያንቀላፋሉና ÷ የሚሰክ
፰፤ ሩም ፡ በሌሊት ፡ ይሰክራሉና ፤ እኛ ፡ ግን ፡ ከቀን ፡
ስለ ፡ ሆንን ÷ የእምነትንና ፡ የፍቅርን ፡ ጥሩር ፡
የመዳንንም ፡ ተስፋ ፡ እንደ ፡ ራስ ፡ ቍር ፡ እየለ
፱፤ በስን ፡ በመጠን ፡ እንኑር ፤ እግዚአብሔር ፡
ለቍጣ ፡ አልመረጠንምና ÷ በጌታችን ፡ በኢየ
ሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ መዳንን ፡ ለማግኘት ፡ ነው ፡
፲፤ እንጂ ። የምንነቃም ፡ ብንሆን ÷ የምናንቀላፋም ፡
ብንሆን ÷ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አብረን ፡ በሕይወት ፡
፲፩፤ እንኖር ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ እኛ ፡ ሞተ ። ስለዚህ ፡ እና
ንተ ፡ ደግሞ ፡ እንደምታደርጉ ÷ እርስ ፡ በርሳ

፫። ፲፫፤ ይሁዳ ፲፬ ።

፬። ፩፤ ፊልጵ ፬ ÷ ፱ ። ፫፤ ፩ ቆሮ ፮ ÷ ፲፰ ፤ ፲፱ ፤ ፳ ። ፭፤ ሮሜ ፩ ÷ ፳፬ ፤ መዝ ፸፱ ÷ ፮ ፤ ኤፌ ፬ ÷ ፲፯–፲፰ ። ፯፤ ፩ ጴጥ ፩ ÷ ፲፭ ። ፰፤ ሉቃ ፲ ÷ ፲፮ ። ፱፤ ኤር ፴፩ ÷ ፴፬ ፤ ዮሐ ፲፫ ÷ ፴፬ ። ፲፩፤ ፪ ተሰ ፫ ÷ ፲፩ ፤ ፲፪ ፤ ኤፌ ፬ ÷ ፳፰ ። ፲፫፤ ፪ ቆሮ ፭ ÷ ፳፰ ። ፲፬፤ ኤፌ ፪ ÷ ፲፪ ። ፲፭፤ ፩ ቆሮ ፲፭ ÷ ፶፩ ፤ ፶፪ ። ፲፮፤ ማቴ ፲፮ ÷ ፳፯ ፤ ፩ ቆሮ ፲፭ ÷ ፶፪ ። ፲፯፤ ዮሐ ፲፬ ÷ ፫ ፤ ፲፯ ÷ ፳፬ ።

፭። ፪፤ ማቴ ፳፬ ÷ ፵፪–፵፬ ። ፫፤ ሉቃ ፲፯ ÷ ፳፮ ፤ ፳፯ ። ፭ ፤ ፮፤ ሮሜ ፲፫ ÷ ፲፩–፲፫ ። ፰፤ ኢሳ ፶፱ ÷ ፲፯ ፤ ኤፌ ፮ ÷ ፲፬ ፤ ፲፯ ። ፱፤ ፪ ተሰ ፪ ÷ ፲፬ ። ፲፤ ሮሜ ፲፬ ÷ ፰ ፤ ፱ ።

ችሁ፡ተመካከሩ፡አንዱም፡አንዱም፡ሌላውን፡ያንጸው ።

፲፪ ፡ ፲፫ ወንድሞች፡ሆይ ÷ ለመካከላችሁ፡የሚደክሙትን፡በጌታም፡የሚገዙአችሁን፡የሚገሥጹአችሁንም፡ታውቁ፡ዘንድ ÷ ስለ፡ሥራቸውም፡በፍቅር፡ከመጠን፡ይልቅ፡ታከብሩአቸው፡ዘንድ፡እንለምናችኋለን ። እርስ፡በርሳችሁ፡በሰላም፡ሁኑ ። ፲፬ ወንድሞች፡ሆይ ÷ እንመክራችኋለን ፤ ያለ፡ሥርዓት፡የሚሄዱትን፡ገሥጹአቸው ፤ ድፍረት፡የሌላቸውን፡አጽኑአቸው ፤ ለደካሞች፡ትጉላቸው ፤ ሰውን፡ሁሉ፡ታገሡ ። ፲፭ ማንም፡ለሌላው፡በክፉ፡ፈንታ፡ክፉ፡እንዳይመልስ፡ተጠንቀቁ ÷ ነገር፡ግን፡ሁልጊዜ፡እርስ፡በርሳችሁ፡ለሁሉም፡መልካሙን፡ስማድረግ፡ትጉ ። ፲፮ ሁልጊዜ፡ደስ፡ይበላችሁ ፤ ፲፯ ፲፰ ሳታቋርጡ፡ጸልዩ ፤ በሁሉ፡አመስግኑ ፤ ይህ፡የእግዚአብሔር፡ፈቃድ፡በክርስቶስ፡ኢየሱስ፡ወደ፡እናንተ፡ነውና ። ፲፱ መንፈስን፡አታጥፉ ፤ ፳ ፡ ፳፩ ትንቢትን፡አትናቁ ፤ ሁሉን፡ፈትኑ፡መልካሙንም፡ያዙ ፤ ፳፪ ከማናቸውም፡ዓይነት፡ክፉ፡ነገር፡ራቁ ።

፳፫ የሰላምም፡አምላክ፡ራሱ፡ሁለንተናችሁን፡ይቀድስ ፤ መንፈሳችሁም፡ነፍሳችሁም፡ሥጋችሁም፡ጌታችን፡ኢየሱስ፡ክርስቶስ፡በመጣ፡ጊዜ፡ያለ፡ነቀፋ፡ፈጽመው፡ይጠበቁ ። ፳፬ የሚጠራችሁ፡የታመነ፡ነው ÷ እርሱም፡ደግሞ፡ያደርገዋል ።

፳፭ ወንድሞች፡ሆይ ÷ ስለ፡እኛ፡ጸልዩ ።

፳፮ ከወንድሞች፡ሁሉ፡ጋር፡በተቀደሰ፡አሳሳም፡ሰላምታ፡ተሰጣጡ ።

፳፯ ይህ፡መልእክት፡ለቅዱሳን፡ወንድሞች፡ሁሉ፡እንዲነበብ፡በጌታ፡አምላችኋለሁ ።

፳፰ የጌታችን፡የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ጸጋ፡ከእናንተ፡ጋር፡ይሁን ፤ አሜን ።

# ሁለተኛይቱ፡የሐዋርያው፡የጳውሎስ፡መልእክት፡ወደ፡ተሰሎንቄ፡ሰዎች ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ ጳውሎስና፡ስልዋኖስ፡ጢሞቴዎስም ÷ በእግዚአብሔር፡በአባታችን፡በጌታ፡በኢየሱስ፡ክርስቶስም፡ወደምትሆን፡ወደ፡ተሰሎንቄ፡ሰዎች፡ቤተ፡ክርስቲያን ፤

፪ ከእግዚአብሔር፡ከአባታችን፡ከጌታ፡ከኢየሱስ፡ክርስቶስም፡ጸጋ፡ሰላምም፡ለእናንተ፡ይሁን ።

፫ ወንድሞች፡ሆይ ÷ እምነታችሁ፡እጅግ፡ስለሚያድግ፡የሁላችሁም፡የእያንዳንዳችሁ፡ፍቅር፡እርስ፡በርሳችሁ፡ስለሚበዛ ÷ ሁልጊዜ፡ስለ፡እናንተ፡እግዚአብሔርን፡እንደሚገባ፡ልናመሰግን፡ግድ፡አለብን ፤ ፬ ስለዚህ፡በምትታገሡበት፡በስደታችሁና፡በመከራችሁ፡ሁሉ፡ከመጽናታችሁና፡ከእምነታችሁ፡የተነሣ፡በእግዚአብሔር፡አብያተ፡ክርስቲያናት፡ስለ፡እናንተ፡ራሳችን፡እንመካለን ።

፭ ስለ፡እርሱ፡ደግሞ፡መከራ፡ለምትቀበሉለት፡ለእግዚአብሔር፡መንግሥት፡የምትበቁ፡ሆናችሁ፡ትቈጠሩ፡ዘንድ ÷ ይህ፡የእግዚአብሔር፡ቅን፡ፍርድ፡ምልክት፡ነው ። ፮ ፡ ፯ ጌታ፡ኢየሱስ፡ከሥልጣኑ፡መላእክት፡ጋር፡ከሰማይ፡በእሳት፡ነበልባል፡ሲገለጥ ÷ መከራን፡ለሚያስጨንቁአችሁ፡መከራን ÷ መከራንም፡ለምትቀበሉ፡ከእኛ፡ጋር፡ዕረፍትን፡ብድራት፡አድርጎ፡እንዲመልስ፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡በእርግጥ፡ጽድቅ፡ነውና ። ፰ እግዚአብሔርን፡የማያውቁትን÷ለጌታችንም፡ለኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ወንጌል፡የማይታዘዙትን፡ይበቀላል ፤ ፱ ፡ ፲ በዚያም፡ቀን፡በቅዱሳኑ፡ሊከብር ÷ ምስክርነታችንንም፡አምናችኋልና፡በሚያምኑት፡ሁሉ፡ዘንድ፡ሊገረም፡ሲመጣ÷ ከጌታ፡ፊት፡ከኃይሉም፡ክብር፡ርቀው፡በዘላለም፡ጥፋት፡ይቀጣሉ ። ፲፩ ፡ ፲፪ ስለዚህም፡ደግሞ፡እንደ፡አምላካችን፡እንደ፡ጌታም፡እንደ፡ኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ጸጋ ÷ የጌታችን፡የኢየሱስ፡ክርስቶስ፡ስም፡በእናንተ፡ዘንድ፡ሊከብር፡እናንተም፡በእርሱ፡ዘንድ፡ልትከብሩ÷አምላካችን፡ለመጥራቱ፡የምትበቁ፡አድርጎ፡ይቍጥራችሁ፡ዘንድ ÷ የበጎነትንም፡ፈቃድ፡ሁሉ፡የእምነትንም፡ሥራ፡በኃይል፡ይፈጽም፡ዘንድ፡ስለ፡እናንተ፡ሁልጊዜ፡እንጸልያለን ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ፡ ፪ ነገር፡ግን ÷ ወንድሞች፡ሆይ ÷ ስለ፡ጌታችን፡ስለ፡ኢየሱስ፡ክርስቶስ፡መምጣትና፡ወደ፡እርሱ፡ስለ፡መሰብሰባችን ÷ በመንፈስ፡

፭ ። ፲፪ ፡ ፲፫ ፤ ፩ ጢሞ· ፭ ÷ ፲፯ ፤ ዕብ· ፲፫ ÷ ፯ ፡ ፲፯ ። ፲፬ ፤ ፪ ተሰ· ፫ ÷ ፲፩ ፡ ፲፭ ። ፲፭ ፤ ምሳ· ፳ ÷ ፳፪ ፤ ፩ ጴጥ· ፫ ÷ ፱ ፤ ሮሜ ፲፪ ÷ ፲፯ ። ፲፮ ፤ ፊልጵ· ፬ ÷ ፬ ። ፲፯ ፤ ሉቃ· ፲፰ ÷ ፩ ። ፲፰ ፤ ኤፌ· ፭ ÷ ፳ ። ፳ ፤ ፩ ቆሮ· ፲፬ ÷ ፩ ። ፳፩ ፤ ኤፌ· ፭ ÷ ፲ ፤ ፩ ዮሐ· ፬ ÷ ፩ ። ፳፬ ፤ ፩ ቆሮ· ፩ ÷ ፱ ፤ ፊልጵ· ፩ ÷ ፮ ። ፳፮ ፤ ፪ ቆሮ· ፲፫ ÷ ፲፪ ።

፩ ። ፩ ፤ ፩ ተሰ· ፩ ÷ ፩ ። ፫ ፤ ቆላ· ፩ ÷ ፬ ። ፬ ፤ ፪ ቆሮ· ፯ ÷ ፬ ፤ ፩ ተሰ· ፪ ÷ ፲፱ ። ፭ ፤ ሉቃ· ፳፩ ÷ ፴፮ ። ፮ ፤ ሮሜ ፲፪ ÷ ፲፱ ። ፯ ፤ ማቴ· ፳፭ ÷ ፴፩ ። ፰ ፤ ኢሳ· ፷፮ ÷ ፲፭ ፤ ሮሜ ፪ ÷ ፰ ። ፱ ፤ ኢሳ· ፪ ÷ ፲ ። ፲ ፤ መዝ· ፹፱ ÷ ፯ ፤ ኢሳ· ፷፮ ÷ ፭ ፤ ራእ· ፯ ÷ ፱—፲፪ ። ፲፪ ፤ ዮሐ· ፲፯ ÷ ፲ ፡ ፳፪ ።

፪ ። ፩ ፤ ፩ ተሰ· ፬ ÷ ፲፭—፲፯ ።

ወይም፡ በቃል፡ ወይም፡ ከእኛ፡ እንደሚመጣ፡ በመልእክት፡— የጌታ፡ ቀን፡ ደርሶአል፡ ብላ ችሁ፥ ከአእምሮአችሁ፡ ቶሎ፡ እንዳትናወጡ፡ እንዳትደነግጡም፡ እንለምናችኋለን። ማንም፡

፫፤ በማናቸውም፡ መንገድ፡ አያስታችሁ፤ ከሀደቱ፡ አስቀድሞ፡ ሳይመጣና፡ የዓመፅ፡ ሰው፡ እር ሱም፡ የጥፋት፡ ልጅ፡ ሳይገለጥ፥ አይደርስ

፬፤ ምና። እኔ፡ እግዚአብሔር፡ ነኝ፡ ብሎ፡ አዋጅ፡ እየነገረ፡ በእግዚአብሔር፡ ቤተ፡ መቅደስ፡ እስ ኪቀመጥ፡ ድረስ፥ አምላክ፡ ከተባለው፡ ሁሉ፥ ሰዎችም፡ ከሚያመልኩት፡ ሁሉ፡ በላይ፡ ራሱን፡ ከፍ፡ ከፍ፡ የሚያደርገው፡ ተቃዋሚ፡ እርሱ፡

፭፤ ነው። ገና፡ ከእናንተ፡ ጋር፡ ሳለሁ፥ ይህን፡

፮፤ እንዳልኋችሁ፡ ትዝ፡ አይላችሁምን? በገዛ፡ ራሱ፡ ጊዜም፡ ይገለጥ፡ ዘንድ፥ የሚከለክለ

፯፤ ውን፡ አሁን፡ ታውቃላችሁ። የዓመፅ፡ ምሥ ጢር፡ አሁን፡ ይሠራልና፤ ብቻ፡ ከመንገድ፡ እስኪወገድ፡ ድረስ፡ አሁን፡ የሚከለክል፡ አለ።

፰፤ በዚያም፡ ጊዜ፡ ጌታ፡ ኢየሱስ፡ በአፉ፡ መንፈስ፡ የሚያጠፋው፥ ሲመጣም፡ በመገለጡ፡ የሚሸ

፱፡፲፤ ረው፡ ዓመፀኛ፡ ይገለጣል፤ ይድኑ፡ ዘንድ፡ የእውነትን፡ ፍቅር፡ ስላልተቀበሉ፡ ለሚጠፉ፥ የእርሱ፡ መምጣት፡ በተአምራት፡ ሁሉና፡ በምልክቶች፡ በሐሰተኞች፡ ድንቆችም፡ በዓ መፅም፡ መታለል፡ ሁሉ፡ እንደ፡ ሰይጣን፡ አሠ

፲፩፡፲፪፤ ራር፡ ነው። ስለዚህም፡ ምክንያት፥ በእውነት፡ ያላመኑ፡ ነገር፡ ግን፡ በዓመፅ፡ ደስ፡ ይላቸው፡ የነበሩ፡ ሁሉ፡ ፍርድን፡ እንዲቀበሉ፥ ሐሰትን፡ ያምኑ፡ ዘንድ፡ እግዚአብሔር፡ የስሕተትን፡ አሠራር፡ ይልክባቸዋል።

፲፫፤ እኛ፡ ግን፥ በጌታ፡ የተወደዳችሁ፡ ወንድ ሞች፡ ሆይ፥ ሁልጊዜ፡ ስለ፡ እናንተ፡ እግዚ አብሔርን፡ ልናመሰግን፡ ግድ፡ አለብን፥ እግ ዚአብሔር፡ በመንፈስ፡ መቀደስ፡ እውነትንም፡ በማመን፡ ለመዳን፡ እንደ፡ በኵራት፡ መርጦአ

፲፬፤ ችኋልና፤ ለዚህም፡ የጌታችንን፡ የኢየሱስ፡ ክርስቶስን፡ ክብር፡ ለማግኘት፡ በወንጌላችን፡

፲፭፤ ጠራችሁ። እንግዲያስ፥ ወንድሞች፡ ሆይ፥ ጸንታችሁ፡ ቁሙ፥ በቃላችንም፡ ቢሆን፡ ወይም፡ በመልእክታችን፡ የተማራችሁትን፡ ወግ፡ ያዙ።

፲፮፡፲፯፤ ራሱ፡ ጌታችን፡ ኢየሱስ፡ ክርስቶስና፡ የወ ደደን፡ በጸጋም፡ የዘላለምን፡ መጽናናት፡ በጎ ንም፡ ተስፋ፡ የሰጠን፡ እግዚአብሔር፡ አባታ ችን፡ ልባችሁን፡ ያጽናኑት፡ በበጎም፡ ሥራና፡ በቃል፡ ሁሉ፡ ያጽኑአችሁ።

ምዕራፍ፡ ፫።

፩፤ በቀረውስ፥ ወንድሞች፡ ሆይ፥ የጌታ፡ ቃል፡ እንዲሮጥ፡ በእናንተም፡ ዘንድ፡ ደግሞ፡ እንደ ሚሆን፡ እንዲከበር፥ እምነትም፡ ለሁሉ፡ ስለማ ይሆን፡ ከዓመፀኞችና፡ ከክፉዎች፡ ሰዎች፡ እን

፫፤ ድንድን፡ ስለ፡ እኛ፡ ጸልዩ። ነገር፡ ግን፡ የሚ ያጸናችሁ፡ ከክፉውም፡ የሚጠብቃችሁ፡ ጌታ፡

፬፤ የታመነ፡ ነው። የምናዝዛችሁንም፡ አሁን፡ እን ድታደርጉ፡ ወደ፡ ፊትም፡ ደግሞ፡ እንድታደ

፭፤ ርጉ፡ ስለ፡ እናንተ፡ በጌታ፡ ታምነናል። ጌታም፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ ፍቅር፡ ወደ፡ ክርስቶስም፡ ትዕግሥት፡ ልባችሁን፡ ያቅናው።

፮፤ ወንድሞች፡ ሆይ፥ ከእኛ፡ እንደ፡ ተቀበለው፡ ወግ፡ ሳይሆን፡ ያለ፡ ሥርዓት፡ ከሚሄድ፡ ወን ድም፡ ሁሉ፡ ትለዩ፡ ዘንድ፡ በጌታችን፡ በኢየ

፯፤ ሱስ፡ ክርስቶስ፡ ስም፡ እናዝዛችኋለን። እኛን፡ ልትመስሉ፡ እንዴት፡ እንደሚገባችሁ፡ ራስ ችሁ፡ ታውቃላችሁና፤ በእናንተ፡ ዘንድ፡ ያለ፡

፰፤ ሥርዓት፡ አልሄድንምና፤ ከእናንተ፡ ዘንድ፡ በአንዱ፡ ስንኳ፡ እንዳንከብድበት፥ ሌሊትና፡ ቀን፡ በድካምና፡ በጥረት፡ እየሠራን፡ እንኖር፡ ነበር፡ እንጂ፥ ከማንም፡ እንጀራን፡ እንዲያው፡

፱፤ አልበላንም። ይህም፡ እኛን፡ ልትመስሉ፡ ራስ ችንን፡ እንደ፡ ምሳሌ፡ እንሰጣችሁ፡ ዘንድ፡ ነበር፡ እንጂ፥ ያለ፡ ሥልጣን፡ ስለ፡ ሆንን፡ አይ

፲፤ ደለም። ደግሞ፡ ከእናንተ፡ ጋር፡ ሳለን፡— ሊሠራ፡ የማይወድ፡ አይብላ፡ ብለን፡ አዘናችሁ፡

፲፩፤ ነበርና። ሥራ፡ ከቶ፡ ሳይሠሩ፥ በሰው፡ ነገር፡ እየገቡ፥ ያለ፡ ሥርዓት፡ ከእናንተ፡ ዘንድ፡ ስለ

፲፪፤ ሚሄዱ፡ ለለ፡ አንዳንዶች፡ ሰምተናልና። እን ደነዚህ፡ ያሉትንም፡ በጸጥታ፡ እየሠሩ፡ የገዛ፡ እንጀራቸውን፡ ይበሉ፡ ዘንድ፡ በጌታችን፡ በኢየ ሱስ፡ ክርስቶስ፡ እናዛቸዋለን፡ እንመክራቸውማ

፲፫፤ ለን። እናንተ፡ ግን፥ ወንድሞች፡ ሆይ፥ መል ካም፡ ሥራን፡ ለመሥራት፡ አትታክቱ።

፲፬፤ በዚህ፡ መልእክት፡ ለተላከ፡ ቃላችን፡ የማ ይታዘዝ፡ ማንም፡ ቢኖር፥ ይህን፡ ተመልከቱት፥ ያፍርም፡ ዘንድ፡ ከእርሱ፡ ጋር፡ አትተባበሩ።

፲፭፤ ነገር፡ ግን፡ እንደ፡ ወንድም፡ ገሥጹት፡ እንጂ፡ እንደ፡ ጠላት፡ አትቍጠሩት።

፲፮፤ የሰላምም፡ ጌታ፡ ራሱ፡ በሁሉ፡ መንገድ፡ ዘወትር፡ ሰላምን፡ ይስጣችሁ። ጌታ፡ ከሁላ ችሁ፡ ጋር፡ ይሁን።

፲፯፤ በገዛ፡ እጄ፡ የተጻፈ፡ የእኔ፡ የጳውሎስ፡ ሰላ ምታ፡ ይህ፡ ነው፤ የመልእክቴ፡ ሁሉ፡ ማስ

፲፰፤ ረጃ፡ ይህ፡ ነው፤ እንዲህ፡ እጽፋለሁ። የጌታ ችን፡ የኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጸጋ፡ ከሁላችሁ፡ ጋር፡ ይሁን።

፪። ፫፤ ፩ ጢሞ. ፬፥፩፤ ፩ ዮሐ. ፪፥፲፰። ፬፤ ዳን. ፲፩፥፴፮። ፰፤ ኢሳ. ፲፩፥፬፤ ራእ. ፲፱፥፲፭። ፱፤ ማቴ. ፳፬፥፳፬፤ ራእ. ፲፫፥፲፫። ፲፤ ፩ ቆሮ. ፩፥፲፰። ፲፩፤ ሮሜ ፩፥፳፰። ፲፪፤ ሮሜ ፩፥፴፪። ፲፫፤ ኤፌ. ፩፥፬፤ ፩ ተሰ. ፩፥፬። ፲፭፤ ፩ ቆሮ. ፲፩፥፪።

፫። ፩፤ ቈላ. ፬፥፫። ፫፤ ፩ ቆሮ. ፲፥፲፫። ፮፤ ማቴ. ፲፰፥፲፯፤ ሮሜ ፲፮፥፲፯፤ ፩ ቆሮ. ፭፥፲፩። ፯፤ ፩ ተሰ. ፩፥፮። ፰፤ ፩ ተሰ. ፪፥፱። ፱፤ ፩ ቆሮ. ፱፥፲፪። ፲፤ ዘፍጥ. ፫፥፲፱። ፲፩፤ ፩ ተሰ. ፬፥፲፩። ፲፪፤ ገላ. ፮፥፱። ፲፬፤ ቲቶ ፫። ፲፭፤ ማቴ. ፲፰፥፲፭። ፲፯፤ ፩ ቆሮ. ፲፮፥፳፩።

# መጀመሪያይቱ ፡ የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ጢሞቴዎስ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ መድኃኒታችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ተስፋች
ንም ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እንዳዘዘው ፡ ትእ
ዛዝ ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሐዋርያ ፡ የሆን ፡
፪፤ ጳውሎስ ÷ በእምነት ፡ እውነተኛ ፡ ልጄ ፡ ለሆን ፡
ለጢሞቴዎስ ፤
ከእግዚአብሔር ፡ ከአባታችን ፡ ከክርስቶስ ፡
ኢየሱስም ፡ ከጌታችን ፡ ጸጋና ፡ ምሕረት ፡ ሰላ
ምም ፡ ይሁን ።

፫፡፬ ወደ ፡ መቄዶንያ ፡ በሄድሁ ፡ ጊዜ ÷ አንዳንዶች ፡
ልዩ ፡ ትምህርትን ፡ እንዳያስተምሩና ፡ ወደ ፡
ተረት ፡ መጨረሻም ፡ ወደሌለው ፡ ወደ ፡ ትው
ልዶች ፡ ታሪክ ፡ እንዳያደምጡ ፡ ልታዘቻቸው ፡
በኤፌሶን ፡ ትቀመጥ ፡ ዘንድ ፡ ለመንሁህ ፤ እንደ ፡
እነዚህ ፡ ያሉ ፡ ነገሮች ፡ ክርክርን ፡ ያመጣሉና ፡
በእምነት ፡ ግን ፡ ላለ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መጋቢ
፭፤ ነት ፡ አይጠቅሙም ። የትእዛዝ ፡ ፍጻሜ ፡ ግን ፡
ከንጹሕ ፡ ልብና ፡ ከበጎ ፡ ሕሊና ፡ ግብዝነትም ፡
ከሌለበት ፡ እምነት ፡ የሚወጣ ፡ ፍቅር ፡ ነው ፤
፮፡፯ ከእነዚህም ፡ አንዳንዶች ፡ ስተው ÷ የሚሉትን ፡
ወይም ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ አስረግጠው ፡ የሚናገ
ሩትን ፡ ሳያስተውሉ ÷ የሕግ ፡ አስተማሪዎች ፡
ሊሆኑ ፡ እየወደዱ ÷ ወደ ፡ ከንቱ ፡ ንግግር ፡ ፈቀቅ ፡
ብለዋል ።

፰፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሰው ፡ እንደሚገባ ፡ ቢሠራበት ፡
ሕግ ፡ መልካም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እናውቃለን ፤
፱፡፲፡፲፩ ይኸውም ÷ ለበደለኞችና ፡ ለማይታዘዙ ÷ ለዓ
መፀኞችና ፡ ለኃጢአተኞች ÷ ቅድስና ፡ ለሌላቸ
ውና ፡ ለርኩሳን ÷ አባትንና ፡ እናትን ፡ ለሚ
ገድሉ ÷ ለነፍሰ ፡ ገዳዮችና ፡ ለሴሰኞች ÷ ከወ
ንድ ፡ ጋርም ፡ ለሚተኙ ÷ በሰዎችም ፡ ለሚነ
ግዱ ÷ ለውሸተኞችም ፡ በውሸትም ፡ ለሚምሉ ÷
የቡሩክ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ክብር ፡ እንደሚ
ገልጥ ፡ ለእኔ ፡ አደራ ፡ እንደ ፡ ተሰጠኝ ፡ ወንጌል ፡
የሆነውን ፡ ደኅና ፡ ትምህርት ፡ ለሚቃወም ፡
ለሌላ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ሕግ ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፡ እንጂ ፡
ለጻድቅ ፡ እንዳልተሠራ ፡ ሲያውቅ ፡ ነው ።

፲፪ ስለ ፡ አገልግሎቱ ፡ ሾሞኝ ፡ ታማኝ ፡ አድርጎ ፡ ስለ ፡
ቈጠረኝ ÷ ኃይል ፡ የሰጠኝን ፡ ክርስቶስ ፡ ኢየሱ
፲፫ ስን ፡ ጌታችንን ፡ አመሰግናለሁ ፤ አስቀድሞ ፡
ተሳዳቢና ፡ አሳዳጅ ፡ አንገላችም ፡ ምንም ፡
ብሆን ÷ ይህን ፡ አደረገልኝ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሳላውቅ ፡
ባለማመን ፡ ስላደረግሁት ፡ ምሕረትን ፡ አገኘሁ ÷
፲፬ የጌታችንም ፡ ጸጋ ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ካለ ፡
ከእምነትና ፡ ከፍቅር ፡ ጋር ፡ እጅግ ፡ በዛ ።
፲፭ ኃጢአተኞችን ፡ ሊያድን ፡ ክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡
ወደ ፡ ዓለም ፡ መጣ ፡ የሚለው ፡ ቃል ፡ የታመነና ፡
ሁሉ ፡ እንዲቀበሉት ፡ የተገባ ፡ ነው ፤ ከኃጢአ
፲፮ ተኞችም ፡ ዋና ፡ እኔ ፡ ነኝ ፤ ስለዚህ ፡ ግን ÷ የዘላ
ለምን ፡ ሕይወት ፡ ለማግኘት ፡ በእርሱ ፡ ያምኑ ፡
ዘንድ ፡ ላላቸው ፡ ሰዎች ፡ ምሳሌ ፡ እንድሆን ÷
ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ዋና ፡ በምሆን ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡
ትዕግሥቱን ፡ ሁሉ ፡ ያሳይ ፡ ዘንድ ÷ ምሕረትን ፡
፲፯ አገኘሁ ። ብቻውን ፡ አምላክ ፡ ለሚሆን ፡ ለማ
ይጠፋው ፡ ለማይታየውም ፡ ለዘመናት ፡ ንጉሥ ፡
ምስጋናና ፡ ክብር ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡
ይሁን ፤ አሜን ።

፲፰ ጢሞቴዎስ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ÷ አስቀድሞ ፡ ስለ ፡
አንተ ፡ እንደ ፡ ተነገረው ፡ ትንቢት ÷ በእርሱ ፡
መልካም ፡ ጦርነት ፡ ትዋጋ ፡ ዘንድ ፡ ይህችን ፡
፲፱ ትእዛዝ ፡ አደራ ፡ እሰጥሃለሁ ፤ እምነትና ፡ በጎ ፡
ሕሊና ፡ ይኑርህ ÷ አንዳንዶች ፡ ሕሊናን ፡ ጥለው ÷
መርከብ ፡ አለ ፡ መሪ ፡ እንደሚጠፋ ÷ በእምነት ፡
፳ ነገር ፡ ጠፍተዋልና ፤ ከእነዚያም ÷ እንዳይሳ
ደቡ ፡ ይማሩ ፡ ዘንድ ፡ ለሰይጣን ፡ አሳልፌ ፡ የሰጠ
ኋቸው ÷ ሄሜኔዎስና ፡ እስክንድሮስ ፡ ናቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፡፪ እንግዲህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በመምሰልና ፡
በጭምትነት ፡ ሁሉ ፡ ጸጥና ፡ ዝግ ፡ ብለን ፡ እን
ድንኖር ÷ ልመናና ፡ ጸሎት ፡ ምልጃም ፡ ምስጋ
ናም ፡ ስለ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ነገሥታትና ፡
ስለ ፡ መኳንንትም ፡ ሁሉ ፡ እንዲደረግ ፡ ከሁሉ ፡
፫፡፬ በፊት ፡ እመክራለሁ ። ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ሊድኑና ፡
እውነቱን ፡ ወደ ፡ ማወቅ ፡ ሊደርሱ ፡ በሚወድ ፡
በእግዚአብሔር ፡ በመድኃኒታችን ፡ ፊት ፡ መል
፭ ካምና ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ይህ ፡ ነው ። አንድ ፡
እግዚአብሔር ፡ አለና ÷ በእግዚአብሔርና ፡ በሰ
ውም ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ መካከለኛው ፡ ደግሞ ፡
አንድ ፡ አለ ÷ እርሱም ፡ ሰው ፡ የሆነ ፡ ክርስቶስ ፡
፮ ኢየሱስ ፡ ነው ፤ ራሱንም ፡ ለሁሉ ፡ ቤዛ ፡ ሰጠ ÷
፯ ይህም ፡ በገዛ ፡ ዘመኑ ፡ ምስክርነቱ ፡ ነበረ ፤ እኔም ፡
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ አዋጅ ፡ ነጋሪና ፡ ሐዋርያ ፡ በእምነ

፩። ፩፤ ሉቃ. ፩ ÷ ፵፯ ፤ ቈላ. ፩ ÷ ፳፯ ። ፪፤ የሐዋ. ፲፮ ÷ ፩ — ፫ ፤ ፩ ቆሮ. ፬ ÷ ፲፯ ፤ ፩ ተሰ. ፫ ÷ ፪ ፤ ቲቶ ፩ ÷ ፬ ፤ ፪ ተሰ. ፩ ÷ ፪ ። ፬፤ ቲቶ ፩ ÷ ፲፬ ፤ ፫ ÷ ፱ ። ፭፤ ሮሜ ፲፫ ÷ ፲ ፤ ፪ ጢሞ. ፪ ÷ ፳፪ ። ፰፤ ሮሜ ፯ ÷ ፲፪ ፤ ፲፮ ። ፱፤ ዘፀአ. ፳፩ ÷ ፲፯ ። ፲፩፤ ገላ. ፪ ÷ ፯ ፤ ቲቶ ፩ ÷ ፫ ። ፲፪፤ የሐዋ. ፱ ÷ ፲፭ ፤ ፳፪ ። ፲፫፤ የሐዋ. ፰ ÷ ፫ ፤ ፳፮ ÷ ፲ ፤ ፲፩ ። ፲፬፤ ማቴ. ፱ ÷ ፲፫ ፤ ሉቃ. ፲፱ ÷ ፲ ። ፲፯፤ ሮሜ ፩ ÷ ፳፫ ፤ ፲፮ ÷ ፳፯ ። ፲፰፤ ፪ ጢሞ. ፪ ÷ ፲፯ ፤ ፬ ÷ ፲፬ ፤ ፩ ቆሮ. ፭ ÷ ፭ ።

፪። ፫፤ ሮሜ. ፩ ÷ ፩ ። ፬፤ ሕዝ. ፲፰ ÷ ፳፫ ፤ ዮሐ. ፫ ÷ ፲፯ ። ፭፤ ገላ. ፫ ÷ ፳ ፤ ዕብ. ፲፪ ÷ ፳፬ ። ፮፤ ማቴ. ፳ ÷ ፳፰ ፤ ቲቶ ፪ ÷ ፲፬ ። ፯፤ ሮሜ. ፩ ÷ ፲፩ ፤ ፪ ጢሞ. ፩ ÷ ፲፩ ፤ ኤፌ. ፫ ÷ ፰ ፤ ፰ ።

ትና፡ በእውነትም፡ የአሕዛብ፡ አስተማሪ፡ ለመ ሆን፡ ተሾምሁ ፤ እውነት፡ እናገራለሁ ፤ አል ዋሽም ።

፰ እንግዲህ፡ ወንዶች፡ በስፍራ፡ ሁሉ፡ ያለ፡ ቍጣና፡ ያለ፡ ክፉ፡ አሳብ፡ የተቀደሱትን፡ እጆች፡ እያነሡ፡ እንዲጸልዩ፡ እፈቅዳለሁ ። ፱ እንዲሁም፡ ደግሞ፡ ሴቶች፡ በሚገባ፡ ልብስ፡ ከእፍረትና፡ ራሳቸውን፡ ከመግዛት፡ ጋር፡ ሰውነታቸውን፡ ይሸልሙ ፤ ፲ እግዚአብሔርን፡ እንፈራለን፡ ለሚሉት፡ ሴቶች፡ እንደሚገባ ፥ መልካም፡ በማድረግ፡ እንጂ፡ በሽሩባና፡ በወርቅ፡ ወይም፡ በዕንቍ፡ ወይም፡ ዋጋው፡ እጅግ፡ በከበረ፡ ልብስ፡ አይሸለሙ ። ፲፩ ሴት፡ በነገር፡ ሁሉ፡ እየተገዛች፡ በዝግታ፡ ትማር ፤ ፲፪ ሴት፡ ግን፡ በዝግታ፡ ትኑር፡ እንጂ፡ ልታስተምር፡ ወይም፡ በወንድ፡ ላይ፡ ልትሠለጥን፡ አልፈቅድም ። ፲፫ አዳም፡ ቀድሞ፡ ተፈጥሮአልና ፥ በኋላም፡ ሔዋን፡ ተፈጠረች ። ፲፬ የተታለለም፡ አዳም፡ አይደለም ፥ ሴቲቱ፡ ግን፡ ተታልላ፡ በመተላለፍ፡ ወደቀች ፤ ፲፭ ነገር፡ ግን፡ ለእምነትና፡ በፍቅር፡ በቅድስናም፡ ራሳቸውን፡ እየገዙ፡ ቢኖሩ፡ በመውለድ፡ ትድናለች ።

## ምዕራፍ፡ ፫ ።

፩ ማንም፡ ኤጲስ፡ ቆጶስነትን፡ ቢፈልግ፡ መልካምን፡ ሥራ፡ ይመኛል፡ የሚለው፡ ቃል፡ የታመነ፡ ነው ። ፪ እንግዲህ፡ ኤጲስ፡ ቆጶስ፡ እንዲህ፡ ሊሆን፡ ይገባዋል ፤ የማይነቀፍ ፥ የአንዲት፡ ሚስት፡ ባል ፥ ልከኛ ፥ ራሱን፡ የሚገዛ ፥ እንደሚገባው፡ የሚሠራ ፥ እንግዳ፡ ተቀባይ ፥ ለማስተማር፡ የሚበቃ ፥ ፫ የማይሰክር ፥ የማይጨቃጨቅ፡ ነገር፡ ግን፡ ገር፡ የሆነ ፥ የማይከራከር ፥ ገንዘብን፡ የማይወድ ፥ ፬ ልጆቹን፡ በጭምትነት፡ ሁሉ፡ እየገዛ፡ የራሱን፡ ቤት፡ በመልካም፡ የሚያስተዳድር ፤ ፭ ሰው፡ ግን፡ የራሱን፡ ቤት፡ እንዲያስተዳድር፡ ባያውቅ ፥ የእግዚአብሔርን፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ እንዴት፡ ይጠብቃታል ? ፮ በትዕቢት፡ ተነፍቶ፡ በዲያብሎስ፡ ፍርድ፡ እንዳይወድቅ ፥ አዲስ፡ ክርስቲያን፡ አይሁን ። ፯ በዲያብሎስ፡ ነቀፋና፡ ወጥመድም፡ እንዳይወድቅ ፥ በውጭ፡ ካሉት፡ ሰዎች፡ ደግሞ፡ መልካም፡ ምስክር፡ ሊኖረው፡ ይገባዋል ።

፰ እንዲሁም፡ ዲያቆናት፡ ጭምቶች ፥ በሁለት፡ ቃል፡ የማይናገሩ ፥ ለብዙ፡ ወይን፡ ጠጅ፡ የማይጐመጁ ፥ ነውረኛ፡ ረብ፡ የማይወዱ ፥ ፱ በንጹሕ፡ ሕሊና፡ የሃይማኖትን፡ ምሥጢር፡ የሚይዙ፡ ሊሆኑ፡ ይገባቸዋል ። ፲ እነዚህም፡ ደግሞ፡ አስቀድመው፡ ይፈተኑ ፥ ከዚያም፡ በኋላ፡ ያለ፡ ነቀፋ፡ ቢሆኑ፡ በዲቁና፡ ሥራ፡ ያገልግሉ ። ፲፩ እንዲሁም፡ ሴቶች፡ ጭምቶች ፥ የማያሙ ፥ ልከኞች ፥ በነገር፡ ሁሉ፡ የታመኑ፡ ሊሆኑ፡ ይገባቸዋል ። ፲፪ ዲያቆናት፡ ልጆቻቸውንና፡ የራሳቸውን፡ ቤቶች፡ በመልካም፡ እየገዙ ፥ እያንዳንዳቸው፡ የአንዲት፡ ሴት፡ ባሎች፡ ይሁኑ ። ፲፫ በዲቁና፡ ሥራ፡ በመልካም፡ ያገለገሉ፡ ለራሳቸው፡ ትልቅ፡ ማዕርግና፡ በክርስቶስ፡ ኢየሱስ፡ ባለው፡ እምነት፡ ብዙ፡ ድፍረት፡ ያገኛሉ ።

፲፬ ፈጥኜ፡ ወደ፡ አንተ፡ እንድመጣ፡ ተስፋ፡ አድርጌ፡ ይህን፡ እጽፍልሃለሁ ። ፲፭ ብዘገይ፡ ግን ፥ በእግዚአብሔር፡ ማደሪያ፡ ቤት፡ መኖር፡ እንዴት፡ እንደሚገባ፡ታውቅ፡ ዘንድ፡ እጽፍልሃለሁ ፤ ቤቱም፡ የእውነት፡ ዓምድና፡ መሠረት ፥ የሕያው፡ እግዚአብሔር፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ ነው ። ፲፮ እግዚአብሔርንም፡ የመምሰል፡ ምሥጢር፡ ያለ፡ ጥርጥር፡ ታላቅ፡ ነው ፤

በሥጋ፡ የተገለጠ ፥
በመንፈስ፡ የጸደቀ ፥
ለመላእክት፡ የታየ ፥
በአሕዛብ፡ የተሰበከ ፥
በዓለም፡ የታመነ ፥
በክብር፡ ያረገ ።

## ምዕራፍ፡ ፬ ።

፩ መንፈስ፡ ግን፡ በግልጥ— በኋለኞች፡ ዘመናት፡ አንዳንዶች፡ የሚያስቱ፡ መናፍስትንና፡ በውሸተኞች፡ ግብዝነት፡ የተሰጠውን፡ የአጋንንትን፡ ትምህርት፡ እያደመጡ ፥ ሃይማኖትን፡ ይክዳሉ፡ ይላል ፤ ፪ በገዛ፡ ሕሊናቸው፡ እንደሚቃጠሉ፡ ደንዝዘው ፥ እነዚህ፡ ውሸተኞች፡ ፫ መጋባትን፡ ይከለክላሉ ፥ አምነውም፡ እውነትን፡ የሚያውቁ፡ ከምስጋና፡ ጋር፡ ይቀበሉ፡ ዘንድ፡ እግዚአብሔር፡ ከፈጠረው፡ መብል፡ እንዲርቁ፡ ያዝዛሉ ። ፬ እግዚአብሔር፡ የፈጠረው፡ ሁሉ፡ መልካም፡ ነውና ፥ ከምስጋናም፡ ጋር፡ ቢቀበሉት፡ የሚጣል፡ ምንም፡ የለም ፤ ፭ በእግዚአብሔር፡ ቃልና፡ በጸሎት፡ የተቀደሰ፡ ነውና ።

፮ ስለዚህ፡ ወንድሞችን፡ ብታሳስብ ፥ በእምነትና፡ በተከተልኸው፡ በመልካም፡ ትምህርት፡ ቃል፡ የምትመገብ፡ የኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ መልካም፡ አገልጋይ፡ ትሆናለህ ። ፯ ነገር፡ ግን፡ ለዚህ፡ ዓለም፡ ከሚመችና፡ የአሮጊቶችን፡ ሴቶች፡ ጨዋታ፡ ከሚመስለው፡ ተረት፡ ራቅ ። እግዚአብሔርን፡ ለመምሰል፡ ግን፡ ራስህን፡ አስለምድ ። ፰ ሰውነትን፡ ለሥጋዊ፡ ነገር፡ ማስለመድ፡ ለጥቂት፡ ይጠቅማልና ፤ እግዚአብሔርን፡ መም

፪ ። ፱ ፩ ጴጥ. ፫፥፫ ። ፲፩ ፩ ቆሮ. ፲፬፥፴፬ ፡ ፴፭ ። ፲፪ ኤፌ. ፭፥፳፪ ። ፲፫ ዘፍጥ. ፪፥፯ ፡ ፳፩ ፡ ፳፪ ። ፲፬ ዘፍጥ. ፫፥፩—፮ ።

፫ ። ፩ የሐዋ. ፳፥፳፰ ። ፪—፭ ፤ ቲቶ ፩፥፯—፱ ። ፯ ፪ ቆሮ. ፰፥፳፩ ። ፰ ፤ ፊልጵ. ፩፥፩ ። ፲፩ ፤ ቲቶ ፪፥፫ ። ፲፭ ፤ ኤፌ. ፪፥፳፩ ፡ ፳፪ ። ፲፮ ፤ ዮሐ. ፩፥፲፬ ፤ ሮሜ ፩፥፬ ፤ ፩ ጴጥ. ፫፥፲፰ ፤ ዮሐ. ፫፥፫ ። ፲፫ ፤ ማቴ. ፳፭፥፴፩ ። ፲፮ ፤ ኤፌ. ፪፥፳፩ ፡ ፳፪ ። ፲፯ ፤ ማቴ. ፳፰፥፲፱ ፤ ቆላ. ፩፥፳ ፡ ፳፫ ፤ ማር. ፲፮፥፲፱ ።

፬ ። ፩ የሐዋ. ፲፱፥፲፯ ፤ ፪ ጢሞ. ፫፥፩ ፤ ፪ ጴጥ. ፫፥፫ ። ፫ ፤ ቆላ. ፪፥፲፮ ፤ ዘፍጥ. ፱፥፫ ፤ ሮሜ ፲፱፥፯ ። ፬ ፤ ዘፍጥ. ፩፥ ፴፩ ፤ የሐዋ. ፲፥፲፭ ። ፯ ፤ ፪ ጢሞ. ፫፥፲፬ ፡ ፲፭ ። ፰ ፤ ፪ ጢሞ. ፪፥፲፮ ፡ ፳፫ ።

ሰል፡ግን፡የአሁንና፡የሚመጣው፡ሕይወት፡
ተስፋ፡ስላለው፥ለነገር፡ሁሉ፡ይጠቅማል ።
፱ ይህ፡ቃል፡የታመነ፡ሁሉም፡እንዲቀበሉት፡
፲ የተገባ፡ነው ፤ ይህን፡ለማግኘት፡እንደክማለ
ንና፥ስለዚህም፡እንሰደባለን ፤ ይህም፡ሰውን፡
ሁሉ፡ይልቁንም፡የሚያምኑትን፡በሚያድን፡
በሕያው፡እምላክ፡ተለፋ፡ስለምናደርግ፡ነው ።
፲፩፲፪ ይህን፡እዘዝና፡አስተምር ። በቃልና፡በኑሮ፡
በፍቅርም፡በእምነትም፡በንጽሕናም፡ለሚያ
ምኑቱ፡ምሳሌ፡ሁን፡እንጂ፥ማንም፡ታናሽነ
፲፫ ትህን፡አይናቀው ። እስክመጣ፡ድረስ፡ለማንበ
ብና፡ለመምከር፡ለማስተማርም፡ተጠንቀቅ ።
፲፬ በትንቢት፡ከሽማግሌዎች፡እጅ፡መጫን፡ጋር፡
የተሰጠህን፥በአንተ፡ያለውን፡የጸጋ፡ስጦታ፡
፲፭ ቸል፡አትበል ። ማደግህ፡በነገር፡ሁሉ፡እንዲ
ገለጥ፡ይህን፡አሰብ፥ይህንም፡እዘውትር ።
፲፮ ለራስህና፡ለትምህርትህ፡ተጠንቀቅ፥በእነዚ
ህም፡ጽና ፤ ይህን፡ብታደርግ፥ራስህንም፡
የሚሰሙህንም፡ታድናለህና ።

ምዕራፍ፡፭ ።

፭፡፩ ሽማግሌ፡የሆነውን፡እትገሥጸው፥እርሱን፡
ግን፡እንደ፡አባት፥ጐበዞችን፡እንደ፡ወንድ
ሞች፥የሽመገሉትን፡ሴቶች፡እንደ፡እናቶች፥
፪ ቈነጃጅቱን፡እንደ፡እኅቶች፡በፍጹም፡ንጽ
ሕና፡ለምናቸው ።
፫ በእውነት፡ባልቴቶች፡የሆኑትን፡ባልቴቶች፡
፬ አክብር ። ማንም፡ባልቴት፡ግን፡ልጆች፡
ወይም፡የልጅ፡ልጆች፡ቢኖሩአት፥እነርሱ፡
አስቀድመው፡ለገዛ፡ቤተ፡ሰዎቻቸው፡እግዚ
አብሔርን፡መምሰል፡ያሰዩ፡ዘንድ፥ለወላጆቻ
ቸውም፡ብድራትን፡ይመልሱላቸው፡ዘንድ፡
ይማሩ ፤ ይህ፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡መልካ
፭ ምና፡የተወደደ፡ነውና ። ብቻዋንም፡ኖራ፡
በእውነት፡ባልቴት፡የምትሆን፡በእግዚአብ
ሔር፡ተስፋ፡ታደርጋለች፥ሌትና፡ቀንም፡በል
፮ መና፡በጸሎትም፡ጸንታ፡ትኖራለች ፤ ቅምጥ
ሊቱ፡ግን፡በሕይወትዋ፡ሳለች፡የሞተች፡ናት ።
፯ ያለ፡ነቀፋ፡እንዲሆኑ፡ይህን፡ደግሞ፡እዘዝ ።
፰ ነገር፡ግን፡ለእርሱ፡ለሆኑት፡ይልቁንም፡
ለለ፡ቤተ፡ሰዎቹ፡የማያስብ፡ማንም፡ቢሆን፥
ሃይማኖትን፡የካደ፡ከማያምንም፡ሰው፡ይልቅ፡
የሚከፋ፡ነው ።
፱ ባልቴት፡በመዝገብ፡ብትጻፍ፡ዕድሜዋ፡
ከስድሳ፡ዓመት፡እንዳያንስ፥የአንድም፡ባል፡
ሚስት፡የነበረች፡እንድትሆን፡ያስፈልጋል ፤
፲ ልጆችን፡በማሳደግ፡እንግዶችንም፡በመቀ
በል፥የቅዱሳንንም፡እግሮች፡በማጠብ፥የተ
ጨነቁትንም፡በመርዳት፡በጎንም፡ሥራ፡ሁሉ፡
በመከተል፥ይህን፡መልካም፡ሥራ፡በማድ
፲፩ ረግ፡የተመሰከረላት፡ልትሆን፡ይገባል ። ባል፡
የሞተባቸውን፡ቈነጃጅት፡ግን፡አትቀበል ፤
በክርስቶስ፡ላይ፡ተነሥተው፡ቢቀማጠሉ፡
፲፪ ሊያገቡ፡ይወዳሉና ፤ የፊተኛውንም፡እምነታ
፲፫ ቸውን፡ስለ፡ናቁ፡ይፈረድባቸዋል ፤ ከዚህም፡
ጋር፡ቤት፡ለቤት፡እየዞሩ፡ሥራን፡መፍታት፡
ደግሞ፡ይማራሉ፥የማይገባውንም፡እየተና
ገሩ፡ለፍላፊዎችና፡በነገር፡ገቢዎች፡ይሆናሉ፡
፲፬ እንጂ፥ሥራ፡ፈቶች፡ብቻ፡አይደሉም ። እን
ግዲህ፡ቈነጃጅት፡ሊያገቡ፥ልጆችንም፡ሊወ
ልዱ፥ቤቶቻቸውንም፡ሊያስተዳድሩ፥ተቃዋ
ሚውም፡የሚሰድብበትን፡አንድን፡ምክንያት፡
፲፭ ስንኳ፡እንዳይሰጡ፡እፈቅዳለሁ ፤ ከአሁን፡
በፊት፡አንዳንዶች፡ሰይጣንን፡እንዲከተሉ፡
፲፮ ፈቀቅ፡ብለዋልና ። ባልቴቶች፡ያሉት፡የሚ
ያምን፡ቢሆን፡ወይም፡የምታምን፡ብትሆን፥
ይርዳአቸው፥ቤተ፡ክርስቲያንም፡እውነተኞ
ችን፡ባልቴቶች፡እንድትረዳ፡አይከብዳባት ።
፲፯ በመልካም፡የሚያስተዳድሩ፡ሽማግሌዎች፥
ይልቁንም፡በመስበክና፡በማስተማር፡የሚደ
፲፰ ክሙት፥እጥፍ፡ክብር፡ይገባቸዋል ። መጽ
ሐፍ፤—የሚያበራየውን፡በሬ፡አፉን፡አት
ሰር፥ደግሞ፤—ለሠራተኛ፡ደመወዙ፡ይገባ
፲፱ ዋል፡ይላልና ። ከሁለት፡ወይም፡ከሦስት፡
ምስክር፡በቀር፡በሽማግሌ፡ላይ፡ክስ፡አትቀ
፳ በል ። ሌሎቹ፡ደግሞ፡እንዲፈሩ፥ኃጢአት፡
፳፩ የሚሠሩትን፡በሁሉ፡ፊት፡ገሥጻቸው ። አን
ድን፡እንኳ፡በአድልዎ፡ሳታደርግ፥እነዚህን፡
ያለ፡መዘንበል፡እንድትጠብቅ፡በእግዚአብሔ
ርና፡በጌታ፡በኢየሱስ፡ክርስቶስ፡በተመረጡ
፳፪ ትም፡መላእክት፡ፊት፡እመክርሃለሁ ። በማ
ንም፡ላይ፡ፈጥነህ፡እጆችህን፡አትጫን፥በሌ
ሎችም፡ኃጢአት፡አትተባበር ፤ ራስህን፡በን
ጽሕና፡ጠብቅ ።
፳፫ ስለ፡ሆድህና፡ስለ፡በሽታህ፡ብዛት፡ጥቂት፡
የወይን፡ጠጅ፡ጠጣ፡እንጂ፥ወደ፡ፊት፡ውኃ፡
ብቻ፡አትጠጣ ።
፳፬ የአንዳንዶች፡ሰዎች፡ኃጢአት፡የተገለጠ፡
ነው፡ፍርድንም፡ያመለክታል፥ሌሎችን፡ግን፡
፳፭ ይከተላቸዋል ፤ እንዲሁ፡መልካም፡ሥራ፡
ደግሞ፡የተገለጠ፡ነው፥ያልተገለጠም፡ከሆነ፡
ሊሰወር፡አይችልም ።

ምዕራፍ፡፮ ።

፮፡፩ የእግዚአብሔር፡ስምና፡ትምህርቱ፡እንዳይ
ሰደብ፥ከቀንበር፡በታች፡ያሉቱ፡ባሪያዎች፡

፬። ፲፡ ምሳ. ፪፥፫፡፱። ፲፪፡ ፪ ጢሞ. ፪፥፳፪፤ ቲቶ ፪፥፯። ፲፬፡ ፪ ጢሞ. ፩፥፮፤ የሐዋ. ፮፥፮፤ ፰፥፲፯። ፲፮፡ የሐዋ. ፳፥፳፰።
፭። ፩፡ ዘሌዋ. ፲፱፥፴፪። ፬፡ ማቴ. ፲፭፥፬፥፮። ፭፡ ሉቃ. ፪፥፴፯። ፮፡ ሮሜ ፩፥፲፫። ፰፡ ቲቶ ፩፥፲፮። ፲፡ ዕብ. ፲፫፥፪፤ ዮሐ. ፲፫፥፲፬። ፲፫፡ ፪ ተሰ. ፫፥፲፩። ፲፬፡ ቲቶ ፪፥፭። ፲፯፡ ሮሜ ፭፥፲፪፤፲፫። ፲፰፡ ዘዳግ. ፳፭፥፬፤ ሉቃ. ፲፥፯፤ ሉቃ. ፲፥፯። ፲፱፡ ዘዳግ. ፲፱፥፲፭። ፳፩፡ ፪ ጢሞ. ፬፥፩። ፳፪፡ ምሳ. ፰፥፲፱፤ ፪ ዮሐ. ፲፥፲፩።
፮። ፩፡ ቲቶ ፪፥፱፡፲።

ሁሉ፡ ለገዡአቸው፡ ጌቶች፡ ክብር፡ ሁሉ፡ እንደ፡ ፪፤ ተገባቸው፡ ይቍጠሩአቸው ። የሚያምኑም፡ ጌቶች፡ ያሉአቸው፥ ወንድሞች፡ ስለ፡ ሆኑ፡ አይናቁአቸው፥ ነገር፡ ግን፡ በመልካም፡ ሥራ ቸው፡ የሚጠቀሙ፡ የሚያምኑና፡ የተወደዱ፥ ስለ፡ ሆኑ፥ ከፊት፡ ይልቅ፡ ያገልግሉ ።

፫፤ እነዚህን፡ አስተምርና፡ ምከር ። ማንም፡ ልዩ፡ ትምህርት፡ የሚያስተምር፡ ከጌታችንም፡ ከኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ በሆነው፡ ጤናማ፡ ቃልና፡ እግዚአብሔርን፡ ለመምሰል፡ በሚስማማ፡ ትም ፬፡፭፤ ህርት፡ የማይጠጋ፡ ቢሆን፥ በትዕቢት፡ ተነፍ ቶአል፡ አንዳችም፡ አያውቅም፥ ነገር፡ ግን፡ ምርመራን፡ በቃልም፡ መዋጋትን፡ እንደ፡ በሽ ተኛ፡ ይናፍቃል ፤ ከእነዚህም፡ ቅንዓትና፡ ክር ክር፡ ስድብም፡ ክፉ፡ አሳብም፡ እርስ፡ በርስ፡ መናደድም፡ ይወጣሉ፥ አእምሮአቸውም፡ በጠ ፉባቸው፡ እውነትንም፡ በተቀሙ፥ አግዚአብ ሔርን፡ መምሰል፡ ማትረፊያ፡ የሚሆን፡ በመ ሰላቸው፡ ሰዎች፡ ይገኛሉ ። እንደነዚህ፡ ከሉት፡ ፮፤ ራቅ ። ኑሮዬ፡ ይበቃኛል፡ ለሚለው፡ ግን፡ እግ ዚአብሔርን፡ መምሰል፡ እጅግ፡ ማትረፊያ፡ ነው፤ ፯፤ ወደ፡ ዓለም፡ ምንም፡ እንኳ፡ አላመጣንምና፥ ፰፤ አንዳችንም፡ ልንወስድ፡ አይቻለንም ፤ ምግ ብና፡ ልብስ፡ ከኖረን፡ ግን፥ እርሱ፡ ይበቃናል ። ፱፤ ዳሩ፡ ግን፡ ባለ፡ ጠጎች፡ ሊሆኑ፡ የሚፈልጉ፡ በጥፋትና፡ በመፍረስ፡ ሰዎችን፡ በሚያሰጥምና፡ በሚያሰንፍ፡ በሚጎዳም፡ በብዙ፡ ምኞትና፡ ፲፤ በፈተና፡ በወጥመድም፡ ይወድቃሉ ። ገንዘ ብን፡ መውደድ፡ የክፉት፡ ሁሉ፡ ሥር፡ ነውና፥ አንዳንዶችም፡ ይህን፡ ሲመኙ፥ ከሃይማኖት፡ ተስስተው፡ በብዙ፡ ሥቃይ፡ ራሳቸውን፡ ወጉ ።

፲፩፤ አንተ፡ ግን፥ የእግዚአብሔር፡ ሰው፡ ሆይ፥ ከዚህ፡ ሽሽ ፤ ጽድቅንና፡ እግዚአብሔርን፡ መምሰል፡ እምነትንም፡ ፍቅርንም፡ መጽናት ንም፡ የዋህነትንም፡ ተከታተል ። መልካሙን፡ ፲፪፤ የእምነት፡ ገድል፡ ተጋደል፥ የተጠራህለትንም፡ በብዙም፡ ምስክሮች፡ ፊት፡ በመልካም፡ መታ መን፡ የታመንህለትን፡ የዘላለምን፡ ሕይወት፡ ያዝ ። ሁሉን፡ በሕይወት፡ በሚጠብቅ፡ በእግዚ ፲፫፤ አብሔር፡ ፊት፥ በጴንጤናዊውም፡ በጲላጦስ፡ ዘንድ፡ መልካሙን፡ መታመን፡ በመሰከረ፡ በክ ርስቶስ፡ ኢየሱስ፡ ፊት፡ አዝሃለሁ ፤ ጌታችን፡ ፲፬፤ ኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ እስኪገለጥ፡ ድረስ፡ ያለ፡ እድፍና፡ ያለ፡ ነቀፋ፡ ሆነህ፡ ትእዛዙን፡ ጠብቅ ፤ ያንም፡ መገለጡን፡ በራሱ፡ ጊዜ፡ ብፁዕና፡ ፲፭፤ ብቻውን፡ የሆነ፡ ገዥ፥ የነገሥታት፡ ንጉሥና፡ የጌቶች፡ ጌታ፥ ያሳያል ። እርሱ፡ ብቻ፡ የማ ፲፮፤ ይሞት፡ ነው ፤ ማንም፡ ሊቀርበው፡ በማይችል፡ ብርሃን፡ ይኖራል ፤ አንድ፡ ሰው፡ እንኳ፡ አላየ ውም፡ ሊያይም፡ አይቻለውም ፤ ለእርሱ፡ ክብ ርና፡ የዘላለም፡ ኃይል፡ ይሁን ፤ አሜን ።

፲፯፤ በአሁኑ፡ ዘመን፡ ባለ፡ ጠጎች፡ የሆኑት፡ የትዕ ቢትን፡ ነገር፡ እንዳያስቡ፥ ደስም፡ እንዲለን፡ ሁሉን፡ አትርፎ፡ በሚሰጠን፡ በሕያው፡ እግ ዚአብሔር፡ እንጂ፡ በሚያልፍ፡ ባለ፡ ጠግነት፡ ፲፰፡፲፱፤ ተስፋ፡ እንዳያደርጉ፡ እዘዛቸው ። እውነተኛ ውን፡ ሕይወት፡ ይይዙ፡ ዘንድ፥ ለሚመጣው፡ ዘመን፡ ለራሳቸው፡ መልካም፡ መሠረት፡ የሚሆ ንላቸውን፡ መዝገብ፡ እየሰበሰቡ፥ መልካምን፡ እንዲያደርጉ፡ በበጎም፡ ሥራ፡ ባለ፡ ጠጎች፡ እን ዲሆኑ፥ ሊረዱና፡ ሊያካፍሉም፡ የተዘጋጁ፡ እን ዲሆኑ፡ ምከራቸው ።

፳፤ ጢሞቴዎስ፡ ሆይ፥ በውሸት፡ እውቀት፡ ከተ ባለ፡ ለዓለም፡ ከሚመች፡ ከከንቱ፡ መለፍለፍና፡ መከራከር፡ እየራቅህ፥ የተሰጠህን፡ አደራ፡ ፳፩፤ ጠብቅ ፤ ይህ፡ እውቀት፡ አለን፡ ብለው፥ አንዳ ንዶች፡ ስለ፡ እምነት፡ ስተዋልና ።

ጸጋ፡ ከአንተ፡ ጋር፡ ይሁን ።

# ሁለተኛይቱ ፡ የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ጢሞቴዎስ ።

ምዕራፍ፡ ፩ ።

፩፤ በክርስቶስ፡ ኢየሱስ፡ እንደሚሆን፡ የሕይ ወት፡ ተስፋ፥ በእግዚአብሔር፡ ፈቃድ፡ የኢ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ሐዋርያ፡ የሆነ፡ ጳውሎስ፥ ፪፤ ለተወደደው፡ ልጁ፡ ለጢሞቴዎስ ፤

ከእግዚአብሔር፡ አብ፡ ከጌታችንም፡ ከክር ስቶስ፡ ኢየሱስ፡ ጸጋና፡ ምሕረት፡ ሰላምም፡ ይሁን ።

፫፤ ሌትና፡ ቀን፡ በልመናዬ፡ ሳላቋርጥ፡ ስለ፡ ማስ ብህ፡ እንደ፡ አበቶቼ፡ አድርጌ፡ በንጹሕ፡ ሕሊና፡ የማመልከውን፡ እግዚአብሔርን፡ አመሰግና ፬፤ ለሁ ፤ እንባህን፡ እያሰብሁ፡ በደስታ፡ እሞላ፡ ፭፤ ዘንድ፡ ላይህ፡ እናፍቃለሁ ። በአንተ፡ ያለውን፡ ግብዝነት፡ የሌለበትን፡ እምነትህን፡ አስበለሁ ፤ ይህም፡ እምነት፡ ቀድሞ፡ በአያትህ፡ በሎይድ፡

፮። ፪፤ ራልም. ፲፯ ። ፫፤ ገላ. ፩፥፱ ። ፬፤ ፪ ጢሞ. ፪፥፲፬፡፳፫ ። ፭፤ ቲቶ ፩፥፲፩፡፲፱፡፲፮ ። ፮፤ ሬልዩ. ፬፥፲፩፡ ዕብ. ፲፫፥፭ ። ፯፤ ኢዮብ ፩፥፳፩ ። ፰፤ ምሳ. ፴፥፰ ። ፱፤ ምሳ. ፲፭፥፳፯፤ ማቴ. ፲፫፥፳፪ ። ፲፤ ሉቃ. ፲፱፥፲፭ ። ፲፩፤ ምሳ. ፲፭፥፱፤ ፪ ጢሞ. ፪፥፳፪ ። ፲፪፤ ፪ ጢሞ. ፬፥፯ ። ፲፫፤ ዮሐ. ፲፰፥፴፯፡፴፯፤ ፲፱፥፲፩ ። ፲፭፤ ዘዳግ. ፲፥፲፯፤ ራእ. ፲፯፥፲፱ ። ፲፯፤ ዘፀአ. ፴፪፥፳፤ ዮሐ. ፩፥፲፰ ። ፲፯፤ ሮሜ ፲፪፥፲፯፤ ሉቃ. ፲፪፥፳ ። ፲፱፤ ማቴ. ፮፥፳ ። ፳፤ ፪ ጢሞ. ፩፥፲፬ ። ፳፩፤ ፪ ጢሞ. ፪፥፲፰ ።

፩። ፩፤ ዮሐ. ፩፥፬ ። ፪፤ ፩ ጢሞ. ፩፥፪ ። ፫፤ የሐዋ. ፳፪፥፫፤ ፳፬፥፲፬፡፲፮ ። ፭፤ የሐዋ. ፲፮፥፩ ።

በእናትህም ፡ በኤውንቄ ፡ ነበረብቸው ÷ በአን
፮ ተም ፡ ደግሞ ፡ እንዳለ ፡ ተረድቼአለሁ ። ስለ
ዚህ ፡ ምክንያት ÷ ለሳት ፡ እንደሚያቀጣጥል ፡
ሰው ÷ እጆቼን ፡ በመጫኔ ፡ በአንተ ፡ ያለውን ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ስጦታ ፡ እንድታነሣሣ ፡ አሳ
፯ ስብሃለሁ ። እግዚአብሔር ፡ የኃይልና ፡ የፍ
ቅር ፡ ራስንም ፡ የመግዛት ፡ መንፈስ ፡ እንጂ ፡
የፍርሃት ፡ መንፈስ ፡ አልሰጠንምና ።

፰ እንግዲህ ፡ ስጌታችን ፡ ምስክርነት ፡ ወይም ፡
ለእስረኛው ፡ ለእኔ ፡ አትፈር ÷ ነገር ፡ ግን ፡ እንደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ኃይል ፡ መጠን ፡ ስለ ፡ ወንጌል ፡
፱ አብረኸኝ ፡ መከራን ፡ ተቀበል ፤ ያዳነን ፡ በቅ
ዱስም ፡ አጠራር ፡ የጠራን ፡ እግዚአብሔር ፡
ነውና ÷ ይህም ፡ እንደ ፡ ራሱ ፡ አሳብና ፡ ጸጋ ፡
መጠን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ ሥራችን ፡ መጠን ፡
አይደለም ፤ ይህም ፡ ጸጋ ፡ ከዘላለም ፡ ዘመናት ፡
፲ በፊት ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ተሰጠን ÷ አሁን ፡
ግን ፡ በመድኃኒታችን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡
መገለጥ ፡ ታይቶአል ። አርሱ ፡ ሞትን ፡ ሽሮአ
ልና ፡ እኔ ፡ ሰባኪና ፡ ሐዋርያ ፡ አሕዛብንም ፡
አስተማሪ ፡ እንድሆን ፡ በተሾምሁበት ፡ በወን
ጌል ፡ ሕይወትንና ፡ አለመጥፋትን ፡ ወደ ፡ ብር
፲፪ ሃን ፡ አውጥቶአል ። ስለዚህም ፡ ምክንያት ፡
ይህን ፡ መከራ ፡ ደግሞ ፡ ተቀብዬአለሁ ÷ ነገር ፡
ግን ፡ አላፍርበትም ፤ ያመንሁትን ፡ አውቃለ
ሁና ÷ የሰጠሁትንም ፡ አደራ ፡ እስከዚያ ፡ ቀን ፡
ድረስ ፡ ሊጠብቅ ፡ እንዲችል ፡ ተረድቼአለሁ ።
፲፫ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ባለ ፡ እምነትና ፡ ፍቅር ፡
አድርገህ ÷ ከእኔ ፡ የሰማኸውን ፡ ጤናማ ፡ ቃል ፡
፲፬ ምሳሌ ፡ ያዝ ፤ መልካሙን ፡ አደራ ፡ በእኛ ፡ በሚ
ኖረው ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ጠብቅ ።

፲፭ በእስያ ፡ ያሉቱ ፡ ሁሉ ፡ ከእኔ ፡ ፈቀቅ ፡ አን
ዳሉ ፡ ታውቃለህ ÷ ከእነርሱም ፡ ፊሎጎስና ፡
፲፮ ሄርሞጌኔስ ፡ ናቸው ። ጌታ ፡ ለሄኔሲፎሩ ፡ ቤተ ፡
ሰዎች ፡ ምሕረትን ፡ ይስጥ ÷ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ አሳር
፲፯ ፎኛልና ፤ በሰንሰለቴም ፡ አላፈረበትም ÷ ነገር ፡
ግን ፡ በሮሜ ፡ በደረ ፡ ጊዜ ፡ ፈልጎ ፡ ፈልጎ ፡ አገ
፲፰ ኘኝ ፤ በዚያን ፡ ቀን ፡ ከጌታ ፡ ምሕረትን ፡ አን
ዲያገኝ ፡ ጌታ ፡ ይስጠው ፤ በኤፌሶንም ፡ እን
ዴት ፡ እንዳገለገለኝ ፡ አንተ ፡ በደኅና ፡ ታውቃ
ለህ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ እንግዲህ ÷ ልጄ ፡ ሆይ ÷ አንተ ፡ በክርስቶስ ፡
፪ ኢየሱስ ፡ ባለው ፡ ጸጋ ፡ በርታ ። ብዙ ፡ ሰዎች ፡
የመሰከሩለትን ፡ ከእኔም ፡ የሰማኸውን ፡ ሌሎ
ችን ፡ ደግሞ ፡ ሊያስተምሩ ፡ ለሚችሉ ፡ ለታመኑ ፡
ሰዎች ፡ አደራ ፡ ስጥ ። እንደ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስ ፫
ቶስ ፡ በጎ ፡ ወታደር ፡ ሆነህ ÷ አብረኸኝ ፡ መከራ ፡
ተቀበል ። የሚዘምተው ፡ ሁሉ ፡ ስጦር ፡ ያስከ ፬
ተተውን ፡ ደስ ፡ ያሰኝ ፡ ዘንድ ፡ ትዳር ፡ በሚገኝ
በት ፡ ንግድ ፡ ራሱን ፡ አያጠላልፍም ። ደግሞም ፡ ፭
በጨዋታ ፡ የሚታገል ፡ ማንም ፡ ቢሆን ÷ እንደ
ሚገባ ፡ አድርጎ ፡ በይታገል ÷ የድሉን ፡ አክሊል ፡
አያገኝም ። የሚደክመው ፡ ገበሬ ፡ ፍሬውን ፡ ፮
ከሚበሉት ፡ መጀመሪያ ፡ እንዲሆን ፡ ይገባዋል ።
የምለውን ፡ ተመልከት ፤ ጌታም ፡ በነገር ፡ ሁሉ ፡ ፯
ማስተዋልን ፡ ይስጥህ ።

በወንጌል ፡ እንደምሰብከው ÷ ከሙታን ፡ የተ ፰
ነሣውን ÷ ከዳዊት ፡ ዘርም ፡ የሆነውን ፡ ኢየሱስ ፡
ክርስቶስን ፡ አስብ ፤ ይህንም ፡ በመስበክ ፡ እንደ ፡ ፱
ክፉ ፡ አድራጊ ፡ እስከታሰር ፡ ድረስ ፡ መከራ ፡
እቀበላለሁ ÷ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ግን ፡ አይ
ታሰርም ። ስለዚህ ፡ እነርሱ ፡ ደግሞ ፡ በክርስ ፲
ቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ያለውን ፡ መዳን ፡ ከዘላለም ፡
ክብር ፡ ጋር ፡ እንዲያገኙ ፡ ስለ ፡ ተመረጡት ፡
በነገር ፡ ሁሉ ፡ እጸናለሁ ። ቃሉ ፡ የታመነ ፡ ነው ፡ ፲፩
እንዲህ ፡ የሚለው ፦— ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ከሞትን ÷
ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ደግሞ ፡ በሕይወት ፡ እንኖራለን ፤
ብንጸና ÷ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ደግሞ ፡ እንነግሣለን ፤ ፲፪
ብንክደው ÷ እርሱ ፡ ደግሞ ፡ ይክደናል ፤ በናም ፲፫
ነው ÷ እርሱ ፡ የታመነ ፡ ሆኖ ፡ ይኖራል ፤ ራሱን ፡
ሊክድ ፡ አይችልምና ።

ይህን ፡ አሳስባቸው ÷ በቃልም ፡ እንዳይጣሉ ፡ ፲፬
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ምከራቸው ÷ ይህ ፡
ምንም ፡ የማይረባ ፡ የሚሰሙትንም ፡ የሚያፈ
ርስ ፡ ነውና ። የእውነትን ፡ ቃል ፡ በቅንነት ፡ ፲፭
የሚናገር ፡ የማያሳፍርም ፡ ሠራተኛ ፡ ሆነህ ÷
የተፈተነውን ፡ ራስህን ፡ ስእግዚአብሔር ፡ ልታ
ቀርብ ፡ ትጋ ። ነገር ፡ ግን ፡ ለዓለም ፡ ከሚመች ፡ ፲፮
ከከንቱ ፡ መለፍለፍ ፡ ራቅ ፤ ኃጢአተኝነታቸ
ውን ፡ ከፊት ፡ ይልቅ ፡ ይጨምራሉና ÷ ቃላቸ ፲፯
ውም ፡ እንደ ፡ ጭንቁር ፡ ይበላል ፤ ከእነርሱም ፡
ሄሜኔዎስና ፡ ፊሊጦስ ፡ ናቸው ፤ እነዚህም ፦— ፲፰
ትንሣኤ ፡ ከአሁን ፡ በፊት ፡ ሆኖአል ፡ እያሉ ÷
ስለ ፡ እውነት ፡ ስተው ÷ የአንዳንዶችን ፡ እምነት ፡
ይገለብጣሉ ። ሆኖም ፦— ጌታ ፡ ለእርሱ ፡ የሆ ፲፱
ኑትን ፡ ያውቃል ÷ ደግሞም ፦— የጌታን ፡ ስም ፡
የሚጠራ ፡ ሁሉ ፡ ከዓመፅ ፡ ይራቅ ፡ የሚለው ፡
ማኅተም ፡ ያለበት ፡ የተደላደለ ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ መሠረት ፡ ቆሞአል ።

በትልቅም ፡ ቤት ፡ የእንጨትና ፡ የሸክላ ፡ ዕቃ ፡ ፳
ደግሞ ፡ አለ ፡ እንጂ ፡ የወርቅና ፡ የብር ፡ ዕቃ ፡
ብቻ ፡ አይደለም ÷ እኵሌቶቹም ፡ ለክብር ÷ እኵ

፩ ። ፭ ፩ ጢሞ. ፬÷፲፬ ። ፮ ሮሜ ፰÷፲፭ ፤ ሉቃ. ፳፬÷፵፱ ። ፰ ማር. ፰÷፴፰ ። ፱ ቲቶ ፫÷፬ ፤ ፭ ። ፲ ፩ ቆሮ. ፲፭÷፳፮ ፤ ፶፬ ፤ ፶፭ ። ፲፩ ፩ ጢሞ. ፪÷፯ ። ፲፪ ፩ ጴጥ. ፬÷፲፱ ። ፲፫ ፩ ጢሞ. ፮÷፫ ፤ ፩÷፲፬ ። ፲፬ ፩ ጢሞ. ፮÷፳ ። ፲፮ ቍ. ፰ ።

፪ ። ፫ ምዕ. ፩÷፰ ። ፭ ፩ ቆሮ. ፱÷፳፭ ። ፮ ፩ ቆሮ. ፱÷፯ ። ፰ ፩ ቆሮ. ፲፭÷፳ ፤ ማቴ. ፩÷፩ ። ፱ ምዕ. ፩÷፰ ፤ ፊልጵ. ፩÷፲፪—፲፬ ። ፲ ቈላ. ፩÷፳፬ ፤ ፪ ቆሮ. ፩÷፮ ። ፲፩ ሮሜ ፮÷፭ ። ፲፪ ሮሜ ፰÷፲፯ ፤ ማቴ. ፲÷፴፫ ። ፲፫ ሮሜ ፫÷፫ ፤ ዘኍል. ፳፫÷፲፱ ። ፲፬ ቲቶ ፫÷፱ ። ፲፮ ፩ ጢሞ. ፬÷፯ ። ፲፯ ፩ ጢሞ. ፩÷፳ ። ፲፱ ፩ ቆሮ. ፲፭÷፲፱ ። ፳ ዘኍል. ፲፮÷፭ ፤ ኢሳ. ፳፰÷፲፮ ። ፳ ሮሜ ፱÷፳፩ ።

፳፩ ሌሎቹም ፡ ለውርደት ፡ ይሆናሉ ፤ እንግዲህ ፡
ማንም ፡ ራሱን ፡ ከእነዚህ ፡ ቢያነጻ ÷ ለክብር ፡
የሚሆን ፡ የተቀደሰም ፡ ለጌታውም ፡ የሚጠ
ቅም ፡ ለበጎም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ የተዘጋጀ ፡ ዕቃ ፡
፳፪ ይሆናል ። ከክፉ ፡ የጕልማስነት ፡ ምኞት ፡ ግን ፡
ሽሽ ÷ በንጹሕም ፡ ልብ ፡ ጌታን ፡ ከሚጠሩ ፡ ጋር ፡
ጽድቅን ፡ እምነትን ፡ ፍቅርን ፡ ሰላምን ፡ እጥብ
፳፫ ቀህ ፡ ተከተል ። ነገር ፡ ግን ፡ ጠብን ፡ እንዲያ
መጣ ፡ አውቀህ ፡ ከስንፎችና ፡ ከልተማሩ ፡ ምር
፳፬ መራ ፡ ራቅ ፤ የጌታም ፡ ባሪያ ፡ ለሰው ፡ ሁሉ ፡
ገር ፡ ለማስተማርም ፡ የሚበቃ ፡ ለትዕግሥትም ፡
የሚጸና ፡ ሊሆን ፡ እንጂ ፡ ሊጣላ ፡ አይገባውም ።
፳፭፡፳፮ ደግሞም ፦ ምናልባት ፡ እግዚአብሔር ፡ እውነ
ትን ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ ንስሐን ፡ ይሰጣቸዋልና ፡
ፈቃዱን ፡ ለማድረግ ፡ በዲያብሎስ ፡ ሕያዋን ፡
ሆነው ፡ ከተያዙበት ፡ ወጥመድ ፡ ወጥተው ÷ ወደ ፡
አእምሮ ፡ ይመለሱ ፡ ብሎ ፡ የሚቃወሙትን ፡
በየዋህነት ፡ ይቅጣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ነገር ፡ ግን ፡ በመጨረሻው ፡ ቀን ፡ የሚያስጨ
፪ ንቅ ፡ ዘመን ፡ እንዲመጣ ፡ ይህን ፡ እወቅ ። ሰዎች ፡
ራሳቸውን ፡ የሚወዱ ፡ ይሆናሉና ÷ ገንዘብን ፡
የሚወዱ ÷ ትምክህተኞች ÷ ትዕቢተኞች ÷ ተሳ
ዳቢዎች ÷ ለወላጆቻቸው ፡ የማይታዘዙ ÷ የማያ
፫ መሰግኑ ÷ ቅድስና ፡ የሌላቸው ÷ ፍቅር ፡ የሌላ
ቸው ÷ ዕርቅን ፡ የማይሰሙ ÷ ሐሜተኞች ÷ ራሳ
ቸውን ፡ የማይገዙ ÷ ጨካኞች ÷ መልካም ፡ የሆ
፬ ነውን ፡ የማይወዱ ÷ ከዳተኞች ÷ ችኩሎች ÷
በትዕቢት ፡ የተነፉ ÷ ከእግዚአብሔር ፡ ይልቅ ፡
፭ ተድላን ፡ የሚወዱ ፡ ይሆናሉ ፤ የአምልኮት ፡
መልክ ፡ አላቸው ፡ ኃይሉን ፡ ግን ፡ ክደዋል ፤ ከእ
፮፡፯ ነዚህ ፡ ደግሞ ፡ ራቅ ። ወደ ፡ ቤቶች ፡ ሾልከው ፡
እየገቡ ÷ ኃጢአታቸው ፡ የተከመረባቸውን ፡
በልዩ ፡ ልዩ ፡ ምኞትንም ፡ የሚወሰዱትን ፡ ሁልጊ
ዜም ፡ እየተማሩ ፡ እውነትን ፡ ወደ ፡ ማወቅ ፡ ሊደ
ርሱ ፡ ከቶ ፡ የማይችሉትን ፡ ሞኞችን ፡ ሴቶች ፡
፰ የሚማርኩ ÷ ከእነዚህ ፡ ዘንድ ፡ ናቸውና ። ኢያ
ኔስና ፡ ኢያንበሬስም ፡ ሙሴን ፡ እንደ ፡ ተቃወ
ሙት ÷ እንዲሁ ፡ እነዚህ ፡ ደግሞ ፡ አእምሮአ
ቸው ፡ የጠፋባቸው ፡ ስለ ፡ እምነትም ፡ የተጣሉ ፡
፱ ሰዎች ፡ ሆነው ÷ እውነትን ፡ ይቃወማሉ ። ዳሩ ፡
ግን ፡ የእነዚያ ፡ ሞኝነት ፡ ደግሞ ፡ ግልጥ ፡ እንደ ፡
ሆነ ÷ ሞኝነታቸው ፡ ለሁሉ ፡ ይገለጣልና ፡ ከፊት ፡
ይልቅ ፡ አይቀናላቸውም ።
፲ አንተ ፡ ግን ፡ ትምህርቴንና ፡ አካሄዴን ፡ አሳ
ቤንም ፡ እምነቴንም ፡ ትዕግሥቴንም ፡ ፍቅሬ
፲፩ ንም ፡ መጽናቴንም ፡ ስደቴንም ፡ መከራዬንም ፡
ተከተልህ ፤ በአንጾኪያና ፡ በኢቆንዮን ፡ በልስ
ጥራንም ፡ የሆነብኝን ፡ የታገሥሁትንም ፡ ስደት ፡
፲፪ ታውቃለህ ፤ ጌታም ፡ ከሁሉ ፡ አዳነኝ ። በእው
ነትም ፡ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ እግዚአብሔርን ፡
እየመሰሉ ፡ ሊኖሩ ፡ የሚወዱ ፡ ሁሉ ፡ ይሰደዳሉ ።
፲፫ ነገር ፡ ግን ፡ ክፉዎች ፡ ሰዎችና ፡ አታላዮች ÷ እያ
ሳቱና ፡ እየሳቱ ÷ በክፋት ፡ እየባሱ ፡ ይሄዳሉ ።
፲፬ አንተ ፡ ግን ፡ በተማርህበትና ፡ በተረዳህበት ፡
ነገር ፡ ጸንተህ ፡ ኑር ÷ ከማን ፡ እንደ ፡ ተማርኸው ፡
፲፭ ታውቃለህና ፤ ከሕፃንነትህም ፡ ጀምረህ ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ኢየሱስን ፡ በማመን ÷ መዳን ፡ የሚገኝበ
ትን ፡ ጥበብ ፡ ሊሰጡህ ፡ የሚችሉትን ፡ ቅዱሳን ፡
፲፮፡፲፯ መጻሕፍትን ፡ አውቀሃል ። የእግዚአብሔር ፡
ሰው ፡ ፍጹምና ፡ ለበጎ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ የተዘጋጀ ፡
ይሆን ፡ ዘንድ ÷ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ያለ
በት ፡ መጽሐፍ ፡ ሁሉ ፡ ለትምህርትና ፡ ለተግ
ሣጽ ፡ ልብንም ፡ ለማቅናት ፡ በጽድቅም ፡ ላለው ፡
ምክር ፡ ደግሞ ፡ ይጠቅማል ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በሕያዋንና ፡ በሙታ
ንም ፡ ሊፈርድ ፡ ባለው ፡ በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ ክር
ስቶስ ፡ ፊት ÷ በመገለጡና ፡ በመንግሥቱም ፡
፪ እመክርሃለሁ ፤ ቃሉን ፡ ስበክ ÷ በጊዜውም ፡
አለጊዜውም ፡ ጽና ÷ ፈጽመህ ፡ እየታገሥህና ፡
፫ እያስተማርህ ÷ ዝለፍና ፡ ገሥጽ ፡ ምከርም ። ሕይ
ወት ፡ የሚገኝበትን ፡ ትምህርት ፡ የማይታገሡ
በት ፡ ዘመን ፡ ይመጣልና ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ጆሮቻቸ
ውን ፡ የሚያሳክክ ፡ ስለ ፡ ሆነ ÷ እንደ ፡ ገዛ ፡ ምኞ
ታቸው ፡ ለራሳቸው ፡ አስተማሪዎችን ፡ ያከማ
፬ ቻሉ ። እውነትንም ፡ ከመስማት ፡ ጆሮቻቸውን ፡
ይመልሳሉ ÷ ወደ ፡ ተረትም ፡ ፈቀቅ ፡ ይላሉ ።
፭ አንተ ፡ ግን ፡ ነገርን ፡ ሁሉ ፡ በልክ ፡ አድርግ ÷
መከራን ፡ ተቀበል ÷ የወንጌል ፡ ሰባኪነትን ፡
ሥራ ፡ አድርግ ÷ አገልግሎትህን ፡ ፈጽም ።
፮ በመሥዋዕት ፡ እንደሚደረግ ÷ የእኔ ፡ ሕይ
ወት ፡ ይሠዋልና ÷ የምሄድበትም ፡ ጊዜ ፡ ደር
፯ ሷል ። መልካሙን ፡ ገድል ፡ ተጋድዬአለሁ ÷
ሩጫውን ፡ ጨርሼአለሁ ÷ ሃይማኖትን ፡ ጠብቄአ
፰ ለሁ ፤ ወደ ፡ ፊት ፡ የጽድቅ ፡ አክሊል ፡ ተዘጋጅ
ቶልኛል ÷ ይህንም ፡ ጻድቅ ፡ ፈራጅ ፡ የሆነው ፡
ጌታ ፡ ያን ፡ ቀን ፡ ለእኔ ፡ ያስረክባል ÷ ደግሞም ፡
መገለጡን ፡ ለሚወዱት ፡ ሁሉ ፡ እንጂ ፡ ለእኔ ፡
ብቻ ፡ አይደለም ።
፱ በቶሎ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንድትመጣ ፡ ትጋ ፤
፲ ዴማስ ፡ የአሁኑን ፡ ዓለም ፡ ወዶ ፡ ትቶኛልና ÷
ወደ ፡ ተሰሎንቄም ፡ ሄዶአል ፤ ቄርቂስም ፡ ወደ ፡
ገላትያ ፡ ቲቶም ፡ ወደ ፡ ድልማጥያ ፡ ሄደዋል ፤

፪። ፳፪፤ ፩ጢሞ. ፮፥፲፩። ፳፫፤ ፩ጢሞ. ፬፥፯። ፳፬፤ ማቴ. ፲፪፥፲፱፡፳። ፳፭፤ ፩ጢሞ. ፪፥፬።
፫። ፩—፱፤ ሮሜ ፩፥፳፱—፴፩። ፭፤ ማቴ. ፯፥፲፭፤ ቲቶ ፩፥፲፮። ፮፤ ቲቶ ፩፥፲፩። ፰፤ ዘፀአ. ፯፥፲፩። ፲፤ ፊልጵ. ፪፥፳፪። ፲፩፤ የሐዋ. ፲፫፥፶፤ ፲፬፥፭፡፮፡፲፱። ፲፪፤ ማቴ. ፲፯፥፳፬። ፲፭፤ ዮሐ. ፭፥፴፱፤ መዝ. ፻፲፱፥፺፱። ፲፯፤ ሮሜ ፲፭፥፬፤ ፪ጴጥ. ፩፥፳፤ ፳፩።
፬። ፩፤ የሐዋ. ፲፥፵፪። ፪፤ ኢሳ. ፶፰፥፩። ፫፤ ፩ጢሞ. ፬፥፩። ፬፤ ፪ተሰ. ፪፥፲፩። ፭፤ ቆላ. ፬፥፲፯። ፮፤ ፊልጵ. ፪፥፲፯። ፯፡፰፤ ፩ጢሞ. ፮፥፲፪፤ ፩ቆሮ. ፱፥፳፬—፳፯። ፲፡፲፩፤ ቆላ. ፬፥፲፡፲፬።

፲፩ ሉቃስ ፡ ብቻ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ አለ ። ማርቆስ ፡ ለአገልግሎት ፡ ብዙ ፡ ይጠቅመኛልና ፡ ይዘኸው ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አምጣው ። ፲፪ ቲኪቆስን ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ኤፌሶን ፡ ላክሁት ። ፲፫ ስትመጣ ፡ በጢሮአዳ ፡ ከአከርጳ ፡ ዘንድ ፡ የተውሁትን ፡ በርኖሱንና ፡ መጻሕፍቱን ፡ ይልቁንም ፡ በብራና ፡ የተጻፉትን ፡ አምጣልኝ ። ፲፬ የናስ ፡ አንጥረኛው ፡ እስክንድሮስ ፡ እጅግ ፡ ክፉ ፡ አደረገብኝ ፤ ጌታ ፡ እንደ ፡ ሥራው ፡ ይመልስለታል ። ፲፭ አንተም ፡ ደግሞ ፡ ከእርሱ ፡ ተጠበቅ ፤ የምንናገረውን ፡ እጅግ ፡ ተቃውሞአልና ። ፲፮ በፊተኛው ፡ሙግቴ ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ አልደረሰልኝም ፤ ሁሉም ፡ ተዉኝ ፡ እንጂ ፤ ይህንም ፡ አይቍጠርባቸው ፤ ፲፯ ዳሩ ፡ ግን ፡ የስብከቱ ፡ ሥራ ፡ በእኔ ፡ እንዲፈጸም ፡ አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ እንዲሰሙት ፤ ጌታ ፡ በእኔ ፡ አጠገብ ፡ ቆሞ ፡ አበረታኝ ፤ ከአንበሳ ፡ አፍም ፡ዳንሁ ። ፲፰ ጌታም ፡ ከክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ያድነኛል ፡ ለሰማያዊው ም ፡ መንግሥት ፡ ይጠብቀኛል ፤ ለእርሱ ፡ ከዘላለም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ክብር ፡ ይሁን ፤ አሜን ።

፲፱ ለጵርስቅላና ፡ ለአቂላ ፡ ለሄኔሲፎሩም ፡ ቤተ ፡ ሰዎች ፡ ሰላምታ ፡ አቅርብልኝ ። ፳ ኤርስጦስ ፡ በቆሮንቶስ ፡ ቀረ ፤ ጥሮፊሞስን ፡ ግን ፡ ታሞ ፡ በሚሊጢን ፡ ተውሁት ። ፳፩ ከክረምት ፡ በፊት ፡ እንድትመጣ ፡ትጋ ። ኤውግሎስና ፡ ጱዴስ ፡ ሊኖስም ፡ ቅላውዲያም ፡ ወንድሞችም ፡ ሁሉ ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡልሃል ።

፳፪ ጌታ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ከመንፈስህ ፡ ጋር ፡ ይሁን ። ጸጋ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፤ አሜን ።

# የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ቲቶ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፡፪ የእግዚአብሔር ፡ ባሪያና ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሐዋርያ ፡ የሆነ ፡ ጳውሎስ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ስተመረጡት ፡ እምነት ፡ እንዲሆንላቸው ፡ በዘላለምም ፡ ሕይወት ፡ ተስፋ ፡ እንደ ፡ አምልኮት ፡ ያለውን ፡ እውነት ፡ እንዲያውቁ ፡ የተላከ ፤ ስለዚህም ፡ ሕይወት ፡ የማይዋሽ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከዘላለም ፡ ዘመናት ፡ በፊት ፡ ተስፋ ፡ ስጠ ፤ ፫ በዘመኑም ፡ ጊዜ ፤ መድኃኒታችን ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘ ፤ ስእኔ ፡ አደራ ፡ በተሰጠኝ ፡ስብከት ፡ ቃሉን ፡ ገለጠ ፤ ፬ ለሃይማኖት ፡ኅብረት ፡ እውነተኛ ፡ ልጅ ፡ ለሚሆን ፡ ለቲቶ ፤

ከእግዚአብሔር ፡ አብ ፡ ከመድኃኒታችንም ፡ ከጌታ ፡ ከኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋና ፡ ምሕረት ፡ ሰላምም ፡ ይሁን ።

፭ ስለዚህ ፡ ምክንያት ፡ የቀረውን ፡ እንድታደራጅ ፡ በየከተማውም ፤ እኔ ፡ አንተን ፡ እንዳዘዝሁ ፤ ሽማግሌዎችን ፡ እንድትሾም ፡ በቀርጤስ ፡ ተውሁህ ፤ ፮ የማይነቀፍና ፡ ያንዲት ፡ ሚስት ፡ ባል ፡ የሚሆን ፤ የሚያምኑም ፡ ልጆች ፡ ያሉት ፤ ስለ ፡ መዳራትም ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አለመታዘዝ ፡ የማይከሰስ ፡ማንም ፡ ቢኖር ፤ ሹመው ። ፯ ኤጲስቆጶስ ፤ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መጋቢ ፤ የማይነቀፍ ፡ ሊሆን ፡ ይገባዋልና ፤ የማይኩራ ፤ የማይቈጣ ፤ የማይሰክር ፤ የማይጨቃጨቅ ፤ ነውረኛ ፡ ረብ ፡ የማይወድ ፤ ፰ ነገር ፡ ግን ፡ እንግዳ ፡ ተቀባይ ፤ በጎ ፡ የሆነውን ፡ ነገር ፡ የሚወድ ፤ ጠንቃቃ ፤ጻድቅ ፤ ቅዱስ ፤ ራሱን ፡ የሚገዛ ፡ ይሁን ፤ ፱ ሕይወት ፡ በሚገኝበት ፡ ትምህርት ፡ ደግሞ ፡ ሊመክር ፡ ተቃዋሚዎቹንም ፡ ሊወቅስ ፡ ይችል ፡ ዘንድ ፤ እንደ ፡ ተማረው ፡ በታመነ ፡ ቃል ፡ ይጽና ። ፲ የማይታዘዙና ፡ ከንቱ ፡ የሚናገሩ ፡ የሚያታልሉም ፡ ይልቁንም ፡ ከተገረዙት ፡ ወገን ፡ የሚሆኑ ፡ ብዙ ፡ ናቸውና ፤ ፲፩ እነዚህም ፡ ስለ ፡ ነውረኛ ፡ ረብ ፡ የማይገባውን ፡ እያስተማሩ ፡ ቤቶችን ፡ በሞላው ፡ ስለሚገለብጡ ፤ አፋቸውን ፡ መዝጋት ፡ ይገባል ። ፲፪ የገዛ ፡ ራሳቸው ፡ ነቢይ ፡ የሆነ ፡ ከእነርሱ ፡ አንዱ ፦ የቀርጤስ ፡ ሰዎች ፡ዘወትር ፡ ውሸተኞች ፤ ክፉዎች ፡ አራዊት ፤ በላተኞች ፤ ሥራ ፡ ፈቶች ፡ ናቸው ፡ ብሎአል ። ፲፫፡፲፬ ይህ ፡ ምስክር ፡ እውነተኛ ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ ምክንያት ፡ የአይሁድን ፡ ተረትና ፡ ከእውነት ፡ ፈቀቅ ፡ የሚሉትን ፡ ሰዎች ፡ ትእዛዝ ፡ሳያዳምጡ ፤ በሃይማኖት ፡ ጤናሞች ፡ እንዲሆኑ ፡ በብርቱ ፡ውቀሳቸው ። ፲፭ ሁሉ ፡ ለንጹሖች ፡ ንጹሕ ፡ ነው ፤ ለርኵሳንና ፡ ለማያምኑ ፡ ግን ፡ ንጹሕ ፡ የሆነ ፡ ምንም ፡ የለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አእምሮአቸውም ፡ሕሊናቸውም ፡ ረክሶአል ። ፲፮ እግዚአብሔርን ፡ እንዲያውቁ ፡ በግልጥ ፡ ይናገራሉ ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ የሚያስጸይፉና ፡ የማይታዘዙ ፡ ለበጎ ፡ ሥራም ፡ ሁሉ ፡ የማይበቁ ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፤ በሥራቸው ፡ ይክዱታል ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ አንተ ፡ ግን ፡ ሕይወት ፡ ለሚገኝበት ፡ ትምህርት ፡ የሚገባውን ፡ ተናገር ። ፪ ሽማግሌዎች ፡ ልከኞች ፤ ጭምቶች ፤ ራሳቸውን ፡ የሚገዙ ፤

፬። ፲፩፤ ቆላ. ፬፥፲ ። ፲፪፤ ፩ ጢሞ. ፩፥፫፤ ፪ ሳሙ. ፫፥፴፱ ። ፲፯፤ የሐዋ. ፳፫፥፲፩ ። ፲፰፤ የሐዋ. ፳፫፥፲፩ ። ፲፱፤ ሮሜ ፲፮፥፴ ። ፲፱፤ ም. ፩፥፲፮፤ የሐዋ. ፲፰፥፪ ። ፳፤ የሐዋ. ፳፥፬፤ ፳፩፥፳፱ ።

፩። ፪፤ ፪ ጢሞ. ፪፥፲፫ ። ፫፤ ፩ ጢሞ. ፩፥፩፡፲፩ ። ፬፤ ፪ ጢሞ. ፩፥፪ ። ፭፤ የሐዋ. ፲፬፥፳፫ ። ፮—፰፤ ፩ ጢሞ. ፫፥፪—፯ ። ፱፤ ፪ ተሰ. ፪፥፲፭ ። ፲፩፤ ፩ ጢሞ. ፮፥፭ ። ፲፫፤ ፩ ጢሞ. ፩፥፯ ። ፲፬፤ ፩ ጢሞ. ፩፥፬ ። ፲፭፤ ሮሜ ፲፬፥፳ ። ፲፮፤ ፪ ጢሞ. ፫፥፭ ።

በእምነትና ፡ በፍቅር ፡ በመጽናትም ፡ ጤናሞች ፡
፫ እንዲሆኑ ፡ ምከራቸው ፤ እንዲሁም ፡ አሮጊ
ቶች ፡ ሴቶች ፡ አካሄዳቸው ፡ ለቅዱስ ፡ አገልግ
ሎት ፡ የሚገባ ፥ የማያሙ ፥ ስብዙ ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡
የማይገዙ ፥ በጎ ፡ የሆነውን ፡ ነገር ፡ የሚያስተ
፬፡፭ ምሩ ፡ ይሁኑ ፤ ቈነጃጅትም ፥ የእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ እንዳይሰደብ ፥ በሎቻቸውን ፡ የሚወዱ ፥
ልጆቻቸውን ፡ የሚወዱ ፥ ራሳቸውን ፡ የሚገዙ ፥
ንጹሖች ፥ በቤት ፡ የሚሠሩ ፥ በጎዎች ፥ ለባሎቻ
ቸው ፡ የሚታዘዙ ፡ እንዲሆኑ ፡ ይምከሩአቸው ።
፮ ጎበዞችም ፡ እንዲሁ ፡ ራሳቸውን ፡ እንዲገዙ ፡
፯፡፰ ምከራቸው ። የሚቃወም ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ እኛ ፡
የሚናገረውን ፡ መጥፎ ፡ ነገር ፡ ሲያጣ ፡ እንዲያ
ፍር ፥ በነገር ፡ ሁሉ ፡ መልካምን ፡ በማድረግህ ፡
ምሳሌ ፡ የሚሆን ፡ ራስህን ፡ አሳይ ፤ በትምህር
ትህም ፡ ደኅንነትን ፥ ጭምትነትን ፥ ጤናማና ፡
፱፡፲ የማይነቀፍ ፡ ንግግርን ፡ ግለጥ ። ባሪያዎች ፡ በሁ
መድኀኒታችን ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚሆን
ውን ፡ ትምህርት ፡ በሁሉ ፡ ነገር ፡ ያስመሰግኑ ፡
ዘንድ ፥ ለገዛ ፡ ጌቶቻቸው ፡ እንዲገዙ ፡ በሁሉም ፡
ደስ ፡ እንዲያሰኙ ፥ ሳይቃወሙና ፡ ሳይሰርቁም ፡
በጎ ፡ ታማኝነትን ፡ ሁሉ ፡ እንዲያሳዩ ፡ ምከራ
ቸው ።

፲፩ ሰዎችን ፡ ሁሉ ፡ የሚያድን ፡ የእግዚአብሔር ፡
፲፪፡፲፫ ጸጋ ፡ ተገልጦአልና ፤ ይህም ፡ ጸጋ ፥ ኃጢአተኛ
ነትንና ፡ ዓለማዊን ፡ ምኞት ፡ ክደን ፥ የተባረከ
ውን ፡ ተስፋችንን ፡ እርሱም ፡ የታላቁን ፡ የአም
ላካችንንና ፡ የመድኀኒታችንን ፡ የኢየሱስ ፡ ክር
ስቶስን ፡ ክብር ፡ መገለጥ ፡ እየጠበቅን ፥ ራሳች
ንን ፡ በመግዛትና ፡ በጽድቅ ፡ እግዚአብሔርንም ፡
በመምሰል ፡ በአሁኑ ፡ ዘመን ፡ እንድንኖር ፡ ያስ
፲፬ ተምረናል ፤ መድኀኒታችንም ፡ ከዓመፅ ፡ ሁሉ ፡
እንዲቤዠን ፥ መልካሙንም ፡ ለማድረግ ፡ የሚ
ቀናውን ፡ ገንዘቡም ፡ የሚሆነውን ፡ ሕዝብ ፡
ለራሱ ፡ እንዲያነጻ ፥ ስለ ፡ እኛ ፡ ነፍሱን ፡ ሰጥቶ
አል ።

፲፭ ይህን ፡ በሙሉ ፡ ሥልጣን ፡ ተናገርና ፡ ምከር ፡
ገሥጽም ፤ ማንም ፡ አይናቅህ ።

ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፡፪ ለገዦችና ፡ ለባለ ፡ ሥልጣኖች ፡ የሚገዙና ፡
የሚታዘዙ ፥ ለበጎ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ የተዘጋጁ ፥
ማንንም ፡ የማይሰድቡ ፥ የማይከራከሩ ፥ ገሮች ፥
ለሰው ፡ ሁሉ ፡ የዋህነትን ፡ ሁሉ ፡ የሚያሳዩ ፡
፫ እንዲሆኑ ፡ አሳስባቸው ። እኛ ፡ ደግሞ ፡ አስቀ
ድመን ፡ የማናስተውል ፡ ነበርንና ፤ የማንታዘዝ ፥
የምንስት ፥ ለምኞትና ፡ ለልዩ ፡ ልዩ ፡ ተድላ ፡
እንደ ፡ ባሪያዎች ፡ የምንገዛ ፥ በክፋትና ፡ በምቀ
ኝነት ፡ የምንኖር ፥ የምንጣላ ፥ እርስ ፡ በርሳችን ፡
፬ የምንጠላላ ፡ ነበርን ። ነገር ፡ ግን ፡ የመድኀኒ
ታችን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቸርነትና ፡ ሰውን ፡
፭ መውደዱ ፡ በተገለጠ ፡ ጊዜ ፥ እንደ ፡ ምሕረቱ ፡
መጠን ፡ ስአዲስ ፡ ልደት ፡ በሚሆነው ፡ መታጠ
ብና ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በመታደስ ፡ አዳነን ፡
እንጂ ፥ እኛ ፡ ስላደረግነው ፡ በጽድቅ ፡ በሆ
፮፡፯ ነበረው ፡ ሥራ ፡ አይደለም ፤ ያን ፡ መንፈስም ፥
በጸጋው ፡ ጸድቀን ፡ በዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ተስፋ ፡
ወራሾች ፡ እንድንሆን ፥ በመድኀኒታችን ፡ በኢ
የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ አትርፎ ፡ አፈሰ
፰ ሰው ። ቃሉ ፡ የታመነ ፡ ነው ።

እግዚአብሔርንም ፡ የሚያምኑት ፡ በመልካም ፡
ሥራ ፡ በጥንቃቄ ፡ እንዲጸኑ ፥ እነዚህን ፡ አበረ
ግጠህ ፡ እንድትናገር ፡ እፈቅዳለሁ ። ይህ ፡ መል
፱ ካምና ፡ ለሰዎች ፡ የሚጠቅም ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡
ሞኝነት ፡ ክርክር ፡ ምርመራና ፡ ከትውልዶች ፡
ታሪክ ፡ ከክርክርም ፡ ስለ ፡ ሕግም ፡ ከሚሆን ፡
ጠብ ፡ ራቅ ፤ የማይጠቅሙና ፡ ከንቱዎች ፡ ናቸ
፲፡፲፩ ውና ፤ መለያየትን ፡ የሚያነሣ ፡ ሰው ፡ ጠማማ ፡
እንዲሆን ፡ በራሱም ፡ ላይ ፡ ፈርዶ ፡ ኃጢአትን ፡
እንዲያደርግ ፡ አውቀህ ፥ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ሁለት ፡
ጊዜም ፡ ከገሠጽኸው ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ከሚ
መስል ፡ ሰው ፡ ራቅ ።

፲፪ አርጢሞንን ፡ ወይም ፡ ቲኪቆስን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡
ስልክ ፥ ወደ ፡ ኒቆጵልዮን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንድት
መጣ ፡ ትጋ ፤ በዚያ ፡ ልከርም ፡ ቈርጬአለሁና ።
፲፫ ሕግ ፡ አዋቂውን ፡ ዜማስንና ፡ አጵሎስን ፡ ምንም ፡
እንዳይጐድልባቸው ፡ በጕዞአቸው ፡ ተግተህ ፡
፲፬ እርዳ ። ከወገኖቻችንም ፡ ያሉት ፡ ደግሞ ፡ ፍሬ ፡
ቢሶች ፡ ሆነው ፡ እንዳይቀሩ ፥ የግድ ፡ ለሚያስ
ፈልገው ፡ ነገር ፡ በመልካም ፡ ሥራ ፡ እንዲጸኑ ፡
ይማሩ ።

፲፭ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ያሉት ፡ ሁሉ ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡ
ልሃል ። በእምነት ፡ ለሚወዱን ፡ ሰላምታ ፡ አቅ
ርብልን ።

ጸጋ ፡ ከሁላችሁ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፤ አሜን ።

፪። ፫፤ ፩ ጢሞ· ፫ ፥ ፲፩ ። ፭፤ ፩ ጢሞ· ፭ ፥ ፲፬ ። ፯፤ ፩ ጢሞ· ፬ ፥ ፲፪ ። ፰፤ ፩ ጴጥ· ፪ ፥ ፲፪ ። ፱፤ ፩ ጴጥ· ፪ ፥ ፲፰ ። ፲፤ ማቴ· ፭ ፥ ፲፮ ። ፲፩፤ ፩ ዮሐ· ፪ ፥ ፲፪ ። ፲፪፤ ፊልጵ· ፫ ፥ ፳፤ ፪ ጴጥ· ፩ ፥ ፩ ። ፲፬፤ ማቴ· ፳ ፥ ፳፰ ፤ መዝ· ፻፴ ፥ ፰ ፤ ዘፀአ· ፲፱ ፥ ፭ ። ፲፭፤ ፩ ጢሞ· ፬ ፥ ፲፪ ።
፫። ፩፤ ሮሜ ፲፫ ፥ ፩ ። ፪፤ ኤፌ· ፬ ፥ ፴፩ ። ፫፤ ኤፌ· ፪ ፥ ፪ ። ፭፤ ኤፌ· ፪ ፥ ፰ ፤ ፲፤ ፭ ፥ ፳፮ ፤ ዮሐ· ፫ ፥ ፭ ። ፯፤ ኤፌ· ፪ ፥ ፳፰ ፤ የሐዋ· ፪ ፥ ፴፫ ። ፯፤ ሮሜ ፫ ፥ ፳፬ ፤ ፰ ፥ ፲፯ ። ፱፤ ፩ ጢሞ· ፯ ፥ ፬ ። ፲፤ ማቴ· ፲፰ ፥ ፲፭ ፤ ፲፯ ። ፲፪፤ ፪ ጢሞ· ፬ ፥ ፲፪ ። ፲፫፤ የሐዋ· ፲፰ ፥ ፳፬ ። ፲፬፤ ማቴ· ፯ ፥ ፲፱ ።

# የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ፊልሞና ።

፩፤ የክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ እስር ፡ ጳውሎስ ፡ ወንድሙም ፡ ጢሞቴዎስ ÷ ለተወደደውና ፡ አብ ፪፤ ሮን ፡ ለሚሠራ ፡ ለፊልሞና ÷ ለእኅታችንም ፡ ለአፍብያ ÷ ከእኛም ፡ ጋር ፡ እብሮ ፡ ወታደር ፡ ለሆነ ፡ ለአርክጳ ÷ በቤትህም ፡ ላለች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፤

፫፤ ከእግዚአብሔር ፡ ከአባታችን ፡ ከጌታም ፡ ከኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋና ፡ ሰላም ፡ ለእናንተ ፡ ይሁን ።

፬፥፭፤ በጌታ ፡ በኢየሱስ ፡ ዘንድ ፡ በቅዱሳንም ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ ስላለህ ፡ ስለ ፡ ፍቅርህና ፡ ስለ ፡ እምነትህ ፡ ሰምቼ ÷ በጸሎቴ ፡ እያሳሰብሁ ፡ ሁልጊዜ ፡ አም ፮፤ ላኬን ፡ አመሰግናለሁ ፤ የእምነትህም ፡ኅብረት ÷ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ ያለውን ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በማወቅ ÷ ለክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ፍሬ ፡ እንዲያፈራ ፡ ፯፤ እለምናለሁ ፤ የቅዱሳን ፡ ልብ ፡ በአንተ ፡ ሥራ ፡ ስለ ፡ ዐረፈ ÷ ወንድሜ ፡ ሆይ ÷ በፍቅርህ ፡ ብዙ ፡ ደስታንና ፡ መጽናናትን ፡ አግኝቼአለሁና ።

፰፤ ስለዚህ ፡ የሚገባውን ፡ አዝህ ፡ ዘንድ ፡ በክርስቶስ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ብዙ ፡ ድፍረት ፡ ቢኖረኝ ÷ ፱፤ ይልቁንም ፡ እንደዚህ ፡ የሆንሁ ፡ እኔ ፡ ጳውሎስ ፡ ሽማግሌው ÷ አሁንም ፡ ደግሞ ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እስር ፡ የሆንሁ ÷ ስለ ፡ ፍቅር ፡ እለምናለሁ ። ፲፥፲፩፤ አስቀድሞ ፡ በላልጠቀመህ ÷ አሁን ፡ ግን ፡ ለእኔም ፡ ለአንተም ፡ በስሚጠቅም ፡ በእስራቴ ፡ ስለ ፡ ወለድሁት ፡ ስለ ፡ ልጄ ፡ ስለ ፡ አናሲ ፲፪፤ ሞስ ፡ እለምንሃለሁ ። እርሱን ፡ እልከዋለሁ ፤ ፲፫፤ አንተም ፡ ልቤ ፡ እንደሚሆን ፡ ተቀበለው ። እኔስ ፡ በወንጌል ፡ እስራት ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ እንዲያገለግ ፲፬፤ለኝ ፡ ለራሴ ፡ ላስቀረው ፡ እፈቅድ ፡ ነበር ÷ ነገር ፡ ግን ፡ በጎነትህ ፡ በፈቃድህ ፡ እንጂ ፡ በግድ ፡ እንዳይሆን ÷ ሳልማከርህ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ላደርግ ፡ አልወደድሁም ።

፲፭፤ ተቀብለህ ፡ ለዘላለም ፡ እንድትይዘው ፡ ስለ ፲፮፤ ዚህ ፡ ምናልባት ፡ ለጊዜው ፡ ተለይቶሃልና ፤ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ እንደ ፡ ባሪያ ፡ አይሆንም ÷ ነገር ፡ ግን ፡ ለእኔ ፡ በተለየ ፡ የተወደደ ፡ ወንድም ፡ ከሆነ ÷ ለአንተማ ፡ ይልቅ ፡ በሥጋውም ፡ በጌታም ፡ ዘንድ ፡ ከባሪያ ፡ የሚሻል ፡ የተወደደ ፡ ወንድም ፡ እንዴት ፡ አይሆንም ። ፲፯፤ እንግዲህ ፡ እንደ ፡ ባልንጀራ ፡ ብትቈጥረኝ ÷ እንደ ፡ እኔ ፡ አድርገህ ፡ ተቀበለው ። ፲፰፤ በአንዳች ፡ ነገር ፡ የበደለህ ፡ ቢኖር ፡ ግን ፡ ወይም ፡ ብድር ፡ ያለበት ፡ እንደ ፡ ሆነ ÷ ይህን ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ቍጠር ፤ ፲፱፤ እኔ ፡ ጳውሎስ ፡— እኔ ፡ እመልሰዋለሁ ፡ ብዬ ፡ በእጄ ፡ እጽፋለሁ ፤ ከዚህም ፡ በላይ ፡ ለእኔ ፡ የራስህ ፡ ደግሞ ፡ ብድር ፡ እንዳለብህ ፡ አልልህም ። ፳፤ አዎን ÷ ወንድሜ ፡ ሆይ ÷ በጌታ ፡ እኔ ፡ እንድጠቀምብህ ፡ ይሁን ፤ በክርስቶስ ፡ ልቤን ፡ አሳርፍልኝ ።

፳፩፤ ከምልህ ፡ ይልቅ ፡ አብልጠህ ፡ እንድታደርግ ፡ አውቄ ፡ እንድትታዘዝም ፡ ታምኜ ፡ እጽፍልሃለሁ ። ፳፪፤ ደግሞ ፡ ከዚህም ፡ ጋር ፡ የማስተናግጃ ፡ ቤት ፡ አዘጋጅልኝ ፤ በጸሎታችሁ ፡ ለእናንተ ፡ እንድሰጥ ፡ ተስፋ ፡ አደርጋለሁና ።

፳፫፤ በክርስቶስ ፡ ኢየሱስ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ የታሰረ ፡ ፳፬፤ ኤጳፍራ ፡ አብረውኝም ፡ የሚሠሩ ፡ ማርቆስና ፡ አርስጥሮኮስ ፡ ዴማስም ፡ ሉቃስም ፡ ሰላምታ ፡ ያቀርቡልሃል ።

፳፭፤ የጌታችን ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ጸጋ ፡ ከመንፈሳችሁ ፡ ጋር ፡ ይሁን ፤ አሜን ።

# የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ዕብራውያን ።

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ እግዚአብሔር ፡ በብዙ ፡ ዓይነትና ፡ በብዙ ፡ ጐዳና ፡ ለአባቶቻችን ፡ በነቢያት ፡ ፪፤ ተናግሮ ÷ ሁሉን ፡ ወራሽ ፡ ባደረገው ፡ ደግሞም ፡ ዓለማትን ፡ በፈጠረበት ፡ በልጁ ፡ በዚህ ፡ ዘመን ፡ ፫፤ መጨረሻ ፡ ለእኛ ፡ ተናገረን ፤ እርሱም ፡ የክብሩ ፡ መንጸባረቅና ፡ የባሕርዩ ፡ ምሳሌ ፡ ሆኖ ÷ ሁሉን ፡ በሥልጣኑ ፡ ቃል ፡ እየደገፈ ÷ ኃጢአታችንን ፡ በራሱ ፡ ካነጻ ፡ በኋላ ፡ በሰማያት ፡ በግርማው ፡ ቀኝ ፡ ተቀመጠ ፤ ፬፤ ከመላእክት ፡ ይልቅ ፡ እጅግ ፡ የሚበልጥ ፡ ስምን ፡ በወረሰ ፡ መጠን ፡ እንዲሁ ፡ ከእነርሱ ፡ አብልጦ ፡ ይበልጣል ።

፭፤ ከመላእክትስ ፡—

አንተ ፡ ልጄ ፡ ነህ ÷ እኔ ፡ ዛሬ ፡ ወልጄሃለሁ ÷ ደግሞም ፡—

፩፤ ኤፌ. ፫ ÷ ፩ ፤ ፩ ጢሞ. ፩ ÷ ፪ ። ፪፤ ቈላ. ፬ ÷ ፲፯ ። ፫፤ ቲቶ ፩ ÷ ፬ ። ፬፤ ቈላ. ፩ ÷ ፫ ። ፭፤ ኤፌ. ፩ ÷ ፲፭ ። ፯፤ ፊልጵ. ፩ ÷ ፬ ። ፲፤ ፩ ቆሮ. ፬ ÷ ፲፭ ፤ ቈላ. ፬ ÷ ፱ ። ፲፫፤ ኤፌ. ፮ ÷ ፲፱ ፤ ፳ ፤ ቈላ. ፬ ÷ ፫ ። ፲፬፤ ፪ ቆሮ. ፱ ÷ ፯ ። ፲፯፤ ፩ ቆሮ. ፮ ÷ ፳፬ ፤ ማቴ. ፳፫ ÷ ፰ ። ፳፫፤ ቈላ. ፩ ÷ ፲፬ ። ፳፬፤ ቈላ. ፬ ÷ ፲ ፤ ፲፬ ።

፩። ፩፤ ዘኍል. ፲፪ ÷ ፮—፰ ፤ ኢዩ. ፪ ÷ ፳፰ ። ፪፤ መዝ. ፪ ÷ ፰ ፤ ዮሐ. ፩ ÷ ፫ ፤ ቈላ. ፩ ÷ ፲፮ ። ፫፤ ጥበ. ፯ ÷ ፳፮ ፤ ፪ ቆሮ. ፬ ÷ ፬ ፤ ቈላ. ፩ ÷ ፲፭ ፤ ኤፌ. ፩ ÷ ፳ ። ፬፤ ፊልጵ. ፪ ÷ ፱ ። ፭፤ መዝ. ፪ ÷ ፯ ፤ ፪ ሳሙ. ፯ ÷ ፲፬ ።

እኔ፡አባት፡እሆነዋለሁ፡እርሱም፡ልጅ፡
ይሆነኛል፡

፮፤ ያለው፡ከቶ፡ለማን፡ነው? ደግሞም፡በኵርን፡
ወደ፡ዓለም፡ሲያገባ፡—
የእግዚአብሔር፡መላእክት፡ሁሉም፡ለእ
ርሱ፡ይሰገዱ፡

፯፤ ይላል ። ስለ፡መላእክትም፡—
መላእክቱን፡መናፍስት፡አገልጋዮቹንም፡
የእሳት፡ነበልባል፡የሚያደርግ፡

፰፤ ይላል ፤ ስለ፡ልጁ፡ግን፡—
አምላክ፡ሆይ÷ዙፋንህ፡እስከ፡ዘላለም፡
ድረስ፡ይኖራል ፤ የመንግሥትህ፡በትር፡
፱፤ የቅንነት፡በትር፡ነው ። ጽድቅን፡ወደ
ድህ፡ዓመፅንም፡ጠላህ ፤ ስለዚህ፡እግዚ
አብሔር፡አምላክህ፡ከጓደኞችህ፡ይልቅ፡
በደስታ፡ዘይት፡ቀባህ፡

፲፤ ይላል ። ደግሞ፡—
ጌታ፡ሆይ÷አንተ፡ከጥንት፡ምድርን፡
መሠረትህ÷ሰማዮችም፡የእጆችህ፡ሥራ፡
፲፩፤ ናቸው ፤ እነርሱም፡ይጠፋሉ፡አንተ፡ግን፡
ጸንተህ፡ትኖራለህ ፤ ሁሉም፡እንደ፡ልብስ፡
፲፪፤ ያረጃሉ÷እንደ፡መጐናጸፊያም፡ትጠቀልላ
ቸዋለህ፡ይለወጡማል ፤ አንተ፡ግን፡አንተ፡
ነህ÷ዓመቶችህም፡ከቶ፡አያልቁም፡

፲፫፤ ይላል ። ነገር፡ግን፡ከመላእክት፡—
ጠላቶችህን፡የእግርህ፡መረገጫ፡እስክደ
ርግልህ፡ድረስ፡በቀኜ፡ተቀመጥ፡

፲፬፤ ከቶ፡ለማን፡ብሎአል? ሁሉ፡መዳንን፡ይወ
ርሱ፡ዘንድ፡ስላላቸው፡ለማገዝ፡የሚላኩ፡
የሚያገለግሉም፡መናፍስት፡አይደሉምን?

ምዕራፍ፡፪ ።

፩፤ ስለዚህ፡ከሰማነው፡ነገር፡ምናልባት፡እን
ዳንወሰድ÷ለእርሱ፡አብልጠን፡ልንጠነቀቅ፡
፪፤ ያስፈልገናል ። በመላእክት፡የተነገረው፡ቃል፡
ጽኑ፡ከሆነ÷መተላለፍና፡አለመታዘዝም፡
፫፤ ሁሉ፡የጽድቅን፡ብድራት፡ከተቀበለ÷እኛስ፡
እንዲህ፡ያለውን፡ታላቅ፡መዳን፡ቸል፡ብን
ለው÷እንዴት፡እናመልጣለን? ይህ፡በጌታ፡
በመጀመሪያ፡የተነገረ፡ነበርና÷የሰሙትም፡
፬፤ ለእኛ፡አጸኑት÷እግዚአብሔርም፡እርሱ፡ራሱ፡
እንደ፡ፈቀደ፡በምልክትና፡በድንቅ፡ነገር፡በልዩ፡
ልዩ፡ተአምራትም÷መንፈስ፡ቅዱስንም፡በማ
ደል፡አብሮ፡መሰከረለት ።

፭፤ ስለ፡እርሱ፡የምንናገርበትን፡የሚመጣውን፡
ዓለም፡ለመላእክት፡ያስገዛው፡አይደለምና ።
፮፤ ነገር፡ግን፡አንዱ፡በአንድ፡ስፍራ፡—
ታስበው፡ዘንድ፡ሰው፡ምንድር፡ነው?
ወይስ፡ትጐበኘው፡ዘንድ፡የሰው፡ልጅ፡
፯፤ ምንድር፡ነው? ከመላእክት፡ይልቅ፡በጥ
ቂት፡አሳነስኸው ፤ የክብርና፡የምስጋና፡
ዘውድ፡ጫንህለት÷በእጆችህም፡ሥራ፡
፰፤ ላይ፡ሾምኸው ፤ ሁሉን፡ከእግሮቹ፡በታች፡
አስገዛህለት፡

ብሎ፡መሰከረ ። ሁሉን፡ከእርሱ፡በታች፡
በአስገዛ፡ጊዜ፡ያልተገዛለት፡ምንም፡አልተወ
ምና ። አሁን፡ግን፡ሁሉ፡እንደ፡ተገዛለት፡
፱፤ ገና፡አናይም ፤ ነገር፡ግን፡በእግዚአብሔር፡
ጸጋ፡ስለ፡ሰው፡ሁሉ፡ሞትን፡ይቀምስ፡ዘንድ÷
ከመላእክት፡ይልቅ፡በጥቂት፡አንሶ፡የነበረ
ውን፡ኢየሱስን፡ከሞት፡መከራ፡የተነሣ፡የክብ
ርና፡የምስጋናን፡ዘውድ፡ተጭኖ፡እናየዋለን ።
፲፤ ብዙ፡ልጆችን፡ወደ፡ክብር፡ሲያመጣ፡የመ
ዳናቸውን፡ራስ፡በመከራ፡ይፈጽም፡ዘንድ÷
ከእርሱ፡የተነሣ፡ሁሉ፡በእርሱም፡ሁሉ፡ለሆነ÷
፲፩፤ ለእርሱ፡ተገብቶታልና ። የሚቀድሰውና፡የሚ
፲፪፤ ቀደሱት፡ሁሉ፡ከአንድ፡ናቸውና ፤ ስለዚህም፡
ምክንያት፡—
ስምህን፡ለወንድሞቼ፡እነግራቸዋለሁ፡በማ
ኅበርም፡መካከል፡በዜማ፡አመሰግንሃለሁ ፤
፲፫፤ ደግሞም፡—
እኔ፡በእርሱ፡እታመናለሁ ፤
ደግሞም፡—
እነሆኝ፡እኔን፡እግዚአብሔር፡የሰጠኝ
ንም፡ልጆች፡
ሲል፡ወንድሞች፡ብሎ፡ሊጠራቸው፡አያፍ
ርም ።
፲፬፤ እንግዲህ፡ልጆቹ፡በሥጋና፡በደም፡ስለሚ
፲፭፤ ካፈሉ÷እርሱ፡ደግሞ፡በሞት፡ላይ፡ሥልጣን፡
ያለውን፡በሞት፡እንዲሽር÷ይኸውም፡ዲያ
ብሎስ፡ነው÷በሕይወታቸውም፡ሁሉ፡ስለ፡
ሞት፡ፍርሃት፡በባርነት፡ይታሰሩ፡የነበሩትን፡
ሁሉ፡ነጻ፡እንዲያወጣ÷በሥጋና፡በደም፡እን
፲፮፤ ዲሁ፡ተካፈለ ። የአብርሃምን፡ዘር፡ይዘአል፡
እንጂ፡የያዘው፡የመላእክትን፡አይደለም ።
፲፯፤ ስለዚህ፡የሕዝብን፡ኃጢአት፡ለማስተስረይ÷
ለእግዚአብሔር፡በሆነው፡ነገር፡ሁሉ፡የሚም
ርና፡የታመነ፡ሊቀ፡ካህናት፡እንዲሆን÷በነ
ገር፡ሁሉ፡ወንድሞቹን፡ሊመስል፡ተገባው ።
፲፰፤ እርሱ፡ራሱ፡ተፈትኖ፡መከራን፡ስለ፡ተቀበለ፡
የሚፈተኑትን፡ሊረዳቸው፡ይችላልና ።

ምዕራፍ፡፫ ።

፩፤ ስለዚህ÷ከሰማያዊው፡ጥሪ፡ተካፋዮች፡የሆ
ናችሁ፡ቅዱሳን፡ወንድሞች፡ሆይ÷የሃይማኖ
ታችንን፡ሐዋርያና፡ሊቀ፡ካህናት፡ኢየሱስ፡

፩። ፮፤ መዝ. ፺፯፥፯ ። ፯፤ መዝ. ፻፬፥፬ ። ፰፡፱፤ መዝ. ፵፭፥፮፡፯ ። ፲-፲፪፤ መዝ. ፻፪፥፳፭-፳፯ ። ፲፫፤ መዝ. ፻፲፥፩ ። ፲፬፤ ዳን. ፯፥፲፤ መዝ. ፺፩፥፲፩፤ ማቴ. ፲፰፥፲፤ የሐዋ. ፲፪፥፯ ።

፪። ፪፤ የሐዋ. ፯፥፶፫፤ ገላ. ፫፥፲፱፡፳፤ ። ፫፤ ዕብ. ፲፥፳፰፡፳፱፤ ማር. ፩፥፲፬፤ ሉቃ. ፩፥፪ ። ፬፤ ማር. ፲፮፥፳፤ ፩ ቆሮ. ፲፪፥፬፡፲፩ ። ፮-፰፤ መዝ. ፰፥፬-፮ ። ፰፤ ፩ ቆሮ. ፲፭፥፳፯ ። ፱፤ ፊልጵ. ፪፥፯-፱ ። ፲፤ ሮሜ. ፰፥፳፱፤ ሮሜ. ፲፩፥፴፮ ። ፲፩፤ ማቴ. ፳፰፥፲ ። ፲፪፤ መዝ. ፳፪፥፳፪ ። ፲፫፤ ኢሳ. ፰፥፲፯፡፲፰ ። ፲፬፤ ሮሜ. ፰፥፫፤ ፩ ቆሮ. ፲፭፥፶፬-፶፯፤ ፩ ዮሐ. ፫፥፰ ። ፲፮፤ ኢሳ. ፵፩፥፰፡፱ ። ፲፯፤ ፊልጵ. ፪፥፯ ። ፲፰፤ ዕብ. ፬፥፲፭፤ ሉቃ. ፳፪፥፳፰ ።

፪፤ ክርስቶስን ፡ ተመልከቱ ፤ ሙሴ ፡ ደግሞ ፡ በቤቱ ፡
ሁሉ ፡ የታመነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፥ እርሱ ፡ ለሾመው ፡
፫፤ የታመነ ፡ ነበረ ። ቤትን ፡ የሚያዘጋጀው ፡ ከቤቱ ፡
ይልቅ ፡ የሚበልጥ ፡ ክብር ፡ እንዳለው ፡ መጠን ፥
እንዲሁ ፡ እርሱ ፡ ከሙሴ ፡ ይልቅ ፡ የሚበልጥ ፡
፬፤ ክብር ፡ የተገባው ፡ ሆኖ ፡ ተቈጥሮአልና ። እያ
ንዳንዱ ፡ ቤት ፡ በአንድ ፡ ሰው ፡ ተዘጋጅቶአ
ልና ፥ ሁሉን ፡ ያዘጋጀ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡
፭፤ ነው ። ሙሴስ ፡ በኋላ ፡ ስለሚነገረው ፡ ነገር ፡
ምስክር ፡ ሊሆን ፡ በቤቱ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሎሌ ፡
፮፤ የታመነ ፡ ነበረ ፥ ክርስቶስ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ልጅ ፡
በቤቱ ፡ ላይ ፡ የታመነ ፡ ነው ፤ እኛም ፡ የምንደ
ፍርበትን ፡ የምንመካበትንም ፡ ተስፋ ፡ እስከ ፡
መጨረሻው ፡ አጽንተን ፡ ብንጠብቅ ፡ ቤቱ ፡ ነን ።
፯፤ ስለዚህ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ እንደሚል ፡—
፰፡፱፤ ዛሬ ፡ ድምፁን ፡ ብትሰሙት ፥ አባቶቻ
ችሁ ፡ እኔን ፡ የፈተኑበት ፡ የመረመሩበትም ፡
አርባ ፡ ዓመትም ፡ ሥራዬን ፡ ያዩበት ፡ በም
ድረ ፡ በዳ ፡ በፈተና ፡ ቀን ፡ በማስመረር ፡
እንደ ፡ ሆነ ፥ ልባችሁን ፡ እልከኛ ፡ አታድ
፲፤ ርጉ ። ስለዚህ ፡ ያን ፡ ትውልድ ፡ ተቈ
ጣሁ ፡— ዘወትር ፡ በልባቸው ፡ ይስታሉ ፡
፲፩፤ መንገዴን ፡ ግን ፡ አላወቁም ፡ አልሁ ፤ እን
ዲሁ ፡— ወደ ፡ ዕረፍቴ ፡ አይገቡም ፡ ብዬ ፡
በቍጣዬ ፡ ማልሁ ።
፲፪፤ ወንድሞች ፡ ሆይ ፥ ምናልባት ፡ ሕያው ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ የሚያስከዳችሁ ፡ ክፉና ፡ የማያምን ፡
ልብ ፡ ከእናንተ ፡ በአንዳችሁ ፡ እንዳይኖር ፡ ተጠ
፲፫፤ ንቀቁ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከእናንተ ፡ ማንም ፡ በኃጢ
አት ፡ መታለል ፡ እልከኛ ፡ እንዳይሆን ፥ ዛሬ ፡
ተብሎ ፡ ሲጠራ ፡ ሳለ ፥ በእያንዳንዱ ፡ ቀን ፡ እርስ ፡
፲፬፤ በርሳችሁ ፡ ተመካከሩ ፤ የመጀመሪያ ፡ እምነታች
ንን ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ አጽንተን ፡ ብንጠብቅ ፥
፲፭፤ የክርስቶስ ፡ ተካፋዮች ፡ ሆነናልና ፤ እየተባለ ፡—
ዛሬ ፡ ድምፁን ፡ ብትሰሙት ፥ በማስመረር ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ ልባችሁን ፡ እልከኛ ፡ አታድ
ርጉ ።
፲፮፤ ሰምተው ፡ ያስመረሩት ፡ እነማን ፡ ነበሩ ? በሙሴ ፡
ተመርተው ፡ ከግብፅ ፡ የወጡ ፡ ሁሉ ፡ አይደሉ
፲፯፤ ምን ? አርባ ፡ ዓመትም ፡ የተቈጣባቸው ፡ እነ
ማን ፡ ነበሩ ? ሬሳቸው ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የወ
ደቀ ፥ ኃጢአትን ፡ ያደረጉት ፡ እነርሱ ፡ አይደ
፲፰፤ ሉምን ? ካልታዘዙትም ፡ በተር ፡ ወደ ፡ ዕረፍቱ ፡
፲፱፤ እንዳይገቡ ፡ የማለባቸው ፡ እነማን ፡ ነበሩ ? ባለ
ማመናቸውም ፡ ጠንቀ ፡ ሊገቡ ፡ እንዳልተቻላ
ቸው ፡ እናያለን ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩፤ እንግዲህ ፡ ወደ ፡ ዕረፍቱ ፡ ለመግባት ፡ ተስፋ ፡
ገና ፡ ቀርቶልን ፡ ከሆነ ፥ ምናልባት ፡ ከእናንተ ፡
ማንም ፡ የማይበቃ ፡ መስሎ ፡ እንዳይታይ ፡ እን
፪፤ ፍራ ። ለእነዚያ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ተነገረ ፡ ለእኛ ፡
የምስራች ፡ ተሰብኮልናልና ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ የሰ
ሙት ፡ ቃል ፡ ከሰሚዎቹ ፡ ጋር ፡ በእምነት ፡ ስላል
፫፤ ተዋሐደ ፡ አልጠቀማቸውም ። ሥራው ፡ ዓለም ፡
ከተፈጠረ ፡ጀምሮ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ቢፈጸም ፡—
እንዲህ ፡— ወደ ፡ ዕረፍቴ ፡ አይገቡም ፡ ብዬ ፡
በቍጣዬ ፡ ማልሁ ፡
እንዳለ ፥ እኛስ ፡ ያመንን ፡ ወደ ፡ ዕረፍት ፡ እንገ
፬፤ ባለን ። ስለ ፡ ሰባተኛው ፡ ቀን ፡ በአንድ ፡ ስፍራ ፡—
እግዚአብሔርም ፡ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡ ከሥራው ፡
፭፤ ሁሉ ፡ ዐረፈ ፡ ብሎአልና ፤ በዚህ ፡ ስፍራም ፡
፮፤ ደግሞ ፡— ወደ ፡ ዕረፍቴ ፡ አይገቡም ። እንግ
ዲህ ፡ አንዳንዶች ፡ በዚያ ፡ እንዲገቡ ፡ ስለ ፡ ቀሩ ፥
ቀድሞም ፡ የምስራች ፡ የተሰበከላቸው ፡ ባለመ
ታዘዝ ፡ ጠንቅ ፡ ስላልገቡ ፡—
፯፤ ዛሬ ፡ ድምፁን ፡ ብትሰሙት ፡ ልባችሁን ፡
እልከኛ ፡ አታድርጉ ፡
በፊት ፡ እንደ ፡ ተባለ ፥ ይህን ፡ ከሚያህል ፡ ዘመን ፡
በኋላ ፡ በዳዊት ፡ ሲናገር ፡— ዛሬ ፡ ብሎ ፡ አንድ ፡
፰፤ ቀን ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ይቀጥራል ። ኢያሱ ፡ አሳር
ፎአቸው ፡ ኖሮ ፡ ቢሆንስ ፥ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ስለ ፡
፱፤ ሌላ ፡ ቀን ፡ ባልተናገረ ፡ ነበር ። እንግዲያስ ፡ የሰ
ንበት ፡ ዕረፍት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡ ቀር
፲፤ ቶላቸዋል ። ወደ ፡ ዕረፍቱ ፡ የገባ ፥ እግዚአብ
ሔር ፡ ከሥራው ፡ እንዳረፈ ፥ እርሱ ፡ ደግሞ ፡
ከሥራው ፡ አርፎአልና ።
፲፩፤ እንግዲህ ፡ እንደዚያ ፡ እንደ ፡ አለመታዘዝ ፡
ምሳሌ ፡ ማንም ፡ እንዳይወድቅ ፡ ወደዚያ ፡ ዕረ
፲፪፤ ፍት ፡ ለመግባት ፡ እንትጋ ። የእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ ሕያው ፡ ነውና ፥ የሚሠራም ፥ ሁለትም ፡
አፍ ፡ ካለው ፡ ሰይፍ ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ የተሳለ ፡
ነው ፥ ነፍስንና ፡ መንፈስንም ፡ ጅማትንና ፡ ቅል
ጥምንም ፡ እስኪለይ ፡ ድረስ ፡ ይወጋል ፥ የልብ
፲፫፤ ንም ፡ ስሜትና ፡ አሳብ ፡ ይመረምራል ፤ እኛን ፡
በሚቈጣጠር ፡ በእርሱ ፡ ዓይኖቹ ፡ ፊት ፡ ሁሉ ፡
ነገር ፡ የተራቈተና ፡ የተገለጠ ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ በእ
ርሱ ፡ ፊት ፡ የተሰወረ ፡ ፍጥረት ፡ የለም ።
፲፬፤ እንግዲህ ፡ ወደ ፡ ሰማያት ፡ ያለፈ ፡ ትልቅ ፡ ሊቀ ፡
ካህናት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ኢየሱስ ፡ ስላ
ለን ፥ ጸንተን ፡ ሃይማኖታችንን ፡ እንጠብቅ ።
፲፭፤ ከኃጢአት ፡ በቀር ፡ በነገር ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ እኛ ፡
የተፈተነ ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ በድካማችን ፡ ሊራራ
፲፮፤ ልን ፡ የማይችል ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ የለንም ። እን
ግዲህ ፡ ምሕረትን ፡ እንድንቀበል ፡ በሚያስፈ
ልገንም ፡ ጊዜ ፡ የሚረዳንን ፡ ጸጋ ፡ እንድናገኝ ፡
ወደ ፡ ጸጋው ፡ ዙፋን ፡ በእምነት ፡ እንቅረብ ።

፫። ፪፤ ዘኍል. ፲፪ ÷ ፯ ። ፭፤ ቍ. ፪ ። ፯፤ ኤፌ. ፪ ÷ ፳፩ ፡ ፳፪ ። ፯—፲፩፤ መዝ. ፺፭ ÷ ፰—፲፩ ። ፰ ፡ ፱፤ ዘፀአ. ፲፯ ÷ ፯ ፤ ዘኍል. ፳ ÷ ፪—፲፫ ። ፲፩፤ ዘኍል. ፲፬ ÷ ፳፱ ፡ ፴፫ ። ፲፫፤ ሮሜ. ፯ ÷ ፲፩ ። ፲፭፤ ቍ. ፯ ። ፲፯—፲፱፤ ዘኍል. ፲፬ ÷ ፪ ፡ ፳፰—፴፱ ፡ ፴—፴፪ ።
፬። ፫፤ ምዕ. ፫ ÷ ፲፩ ። ፬፤ ዘፍጥ. ፪ ÷ ፪ ። ፯፤ ምዕ. ፫ ÷ ፯ ። ፰፤ ዘዳግ. ፴፩ ÷ ፯ ። ፲፤ ራእ. ፲፬ ÷ ፲፫ ። ፲፪፤ ኢሳ. ፵፱ ÷ ፪ ፤ ኤር. ፳፫ ÷ ፳፱ ። ፲፬፤ ምዕ. ፫ ÷ ፩ ። ፲፭፤ ምዕ. ፪ ÷ ፲፯ ፡ ፲፰ ። ፲፮፤ ኤፌ. ፫ ÷ ፲፪ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ኃጢአት ፡ መባንና ፡ መሥዋዕትን ፡ ሊያቀርብ ፡ ከሰው ፡ ተመርጦ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በሆነው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ይሾማልና ፤ ፪ እርሱ ፡ ራሱም ፡ ደግሞ ፡ ድካምን ፡ ስለሚለብስ ፥ ላልተማሩትና ፡ ለሚስቱት ፡ ሊራራላቸው ፡ ይችላል ፤ ፫ በዚህም ፡ ምክንያት ፡ ስለ ፡ ሕዝብ ፡ እንደሚያቀርብ ፡ እንዲሁ ፡ ስለ ፡ ራሱ ፡ ደግሞ ፡ መሥዋዕትን ፡ ስለ ፡ ኃጢአት ፡ ሊያቀርብ ፡ ይገባዋል ። ፬ እንደ ፡ አሮንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ከተጠራ ፡ በቀር ፡ ማንም ፡ ክብሩን ፡ ለራሱ ፡ የሚወስድ ፡ የለም ።

፭ እንዲሁ ፡ ክርስቶስ ፡ ደግሞ ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ ሊሆን ፡ ራሱን ፡ አላከበረም ፡ ነገር ፡ ግን ፡—

አንተ ፡ ልጄ ፡ ነህ ፡ እኔ ፡ ዛሬ ፡ ወልጄሃለሁ ፡

፮ ያለው ፡ እርሱ ፡ ነው ፤ እንደዚህም ፡ በሌላ ፡ስፍራ ፡ ደግሞ ፡—

አንተ ፡ እንደ ፡ መልከ ፡ ጼዴቅ ፡ ሹመት ፡
ለዘላለም ፡ ካህን ፡ ነህ ፡

ይላል ።

፯ እርሱም ፡ በሥጋው ፡ ወራት ፡ ከሞት ፡ ሊያድነው ፡ ወደሚችል ፡ ከብርቱ ፡ ጩኸትና ፡ ከእንባ ፡ ጋር ፡ ጸሎትንና ፡ ምልጃን ፡ አቀረበ ፥ እግዚአብ ፰ ሔርንም ፡ ስለ ፡ መፍራቱ ፡ ተሰማለት ፤ ምንም ፡ ልጅ ፡ ቢሆን ፥ ከተቀበለው ፡ መከራ ፡ መታዘዝን ፡ ፱፡፲ ተማረ ፤ ከተፈጸመም ፡ በኋላ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ መልከ ፡ ጼዴቅ ፡ ሹመት ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ ተብሎ ፡ ስለ ፡ ተጠራ ፥ ለሚታዘዙለት ፡ ሁሉ ፡ የዘላለም ፡ መዳን ፡ ምክንያት ፡ ሆነላቸው ።

፲፩ ስለ ፡ እርሱም ፡ የምንናገረው ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ አለን ፥ጆሮቻችሁም ፡ ስለ ፡ ፈዘዙ ፡ በቃል ፡ ፲፪ ልንተረጕመው ፡ ጭንቅ ፡ ነው ። ከጊዜው ፡ የተነሣ ፡ አስተማሪዎች ፡ ልትሆኑ ፡ ሲገባችሁ ፥ አንድ ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃላት ፡ መጀመሪያ ፡ ያለውን ፡ የሕፃንነትን ፡ ትምህርት ፡ እንዲያስተምራችሁ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ያስፈልጋችኋልና ፤ የሚያስፈልጋችሁም ፡ ወተት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ፲፫ ጠንካራ ፡ ምግብ ፡ አይደለም ። ወተት ፡ የሚጋት ፡ ሁሉ ፡ ሕፃን ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የጽድቅን ፡ ቃል ፡ ፲፬ አያውቅምና ፤ ጠንካራ ፡ ምግብ ፡ ግን ፡ መልካሙንና ፡ ክፉውን ፡ ለመለየት ፡ በሥራቸው ፡ የስመደ ፡ ልቡና ፡ ላላቸው ፡ ለፍጹማን ፡ ሰዎች ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩፡፪ ስለዚህ ፡ የክርስቶስን ፡ ነገር ፡ መጀመሪያ ፡ የሚናገረውን ፡ ቃል ፡ ትተን ፡ ወደ ፡ ፍጹም ፡ እንሂድ ፤ መሠረትን ፡ ደግመን ፡ አንመሥርት ፥ እርሱም ፡ ከሞተ ፡ ሥራ ፡ ንስሐና ፡ በእግዚአብሔር ፡ እምነት ፥ ስለ ፡ ጥምቀቶችና ፡ እጆችንም ፡ ስለ ፡ መጫን ፡ ስለ ፡ ሙታንም ፡ ትንሣኤ ፡ ስለ ፡ ፫ ዘላለም ፡ ፍርድም ፡ ትምህርት ፡ ነው ። እግዚአብሔርም ፡ ቢፈቅድ ፡ ይህን ፡ እናደርጋለን ። ፬ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ብርሃን ፡ የበራላቸውን ፡ ሰማያዊውንም ፡ ስጦታ ፡ የቀመሱትን ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱ ፭ ስም ፡ ተካፋዮች ፡ ሆነው ፡ የነበሩትን ፡ መልካሙንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃልና ፡ ሊመጣ ፡ ፮ ያለውን ፡ የዓለም ፡ ኃይል ፡ የቀመሱትን ፡ በኋላም ፡ የካዱትን ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ለንስሐ ፡ እነርሱን ፡ ማደስ ፡ የማይቻል ፡ ነው ፤ ለራሳቸው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ልጅ ፡ ይሰቅሉታልና ፡ ያዋርዱትማልና ። ፯ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ በእርስዋ ፡ ላይ ፡ የሚወርደውን ፡ ዝናብ ፡ የምትጠጣ ፡ መሬት ፥ ለሚያርሱአትም ፡ ደግሞ ፡ የምትጠቅምን ፡ አትክልት ፡ የምታበቅል ፥ ከእግዚአብሔር ፡ በረከትን ፡ ታገኛለችና ፤ ፰ እሾህንና ፡ ኵርንችትን ፡ ግን ፡ ብታወጣ ፥ የተጣለች ፡ ናት ፡ ለመረገምም ፡ ትቀርባለች ፥ መጨረሻዋም ፡ መቃጠል ፡ ነው ።

፱ ስለ ፡ እናንተ ፡ ግን ፥ ወዳጆች ፡ ሆይ ፥ ምንም ፡ እንኳ ፡ እንዲሁ ፡ ብንናገር ፥ አብልጦ ፡ የሚሻለውና ፡ ለመዳን ፡ የሚሆነው ፡ እንዲሆንላችሁ ፡ ፲ ተረድተናል ። እግዚአብሔር ፥ ቅዱሳንን ፡ ስላገለገላችሁ ፡ እስከ ፡ አሁንም ፡ ስለምታገለግሉአቸው ፥ ያደረጋችሁትን ፡ ሥራ ፡ ለስሙም ፡ ያሳያችሁን ፡ ፍቅር ፡ ይረሳ ፡ ዘንድ ፡ ዓመፀኛ ፡ ፲፩፡፲፪ አይደለምና ። በእምነትና ፡ በትዕግሥትም ፡ የተስፋውን ፡ ቃል ፡ የሚወርሱትን ፡ እንድትመስሉ ፡ እንጂ ፡ ዳተኞች ፡ እንዳትሆኑ ፥ ተስፋ ፡ እስኪሞላ ፡ ድረስ ፡ እያንዳንዳችሁ ፡ ያን ፡ ትጋት ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ እንድታሳዩ ፡ እንመኛለን ።

፲፫፡፲፬ እግዚአብሔርም ፡ ለአብርሃም ፡ ተስፋ ፡ በሰጠው ፡ ጊዜ ፡— በእውነት ፡ እየባረክሁ ፡ እባርክሃለሁ ፡ እያበዛሁም ፡ አበዛሃለሁ ፡ ብሎ ፥ ከእርሱ ፡ በሚበልጥ ፡ በማንም ፡ ሊምል ፡ ስላልቻለ ፥ ፲፭ በራሱ ፡ ማለ ፤ እንዲሁም ፡ እርሱ ፡ ከታገሠ ፡ ፲፮ በኋላ ፡ ተስፋውን ፡ አገኘ ። ሰዎች ፡ ከእነርሱ ፡ በሚበልጠው ፡ ይምላሉና ፥ ለማስረዳትም ፡ የሆነው ፡ መሐላ ፡ የሙግት ፡ ሁሉ ፡ ፍጻሜ ፡ ይሆናል ፤ ፲፯፡፲፰ ስለዚህም ፡ እግዚአብሔር ፥ የተስፋውን ፡ ቃል ፡ ለሚወርሱ ፡ ፈቃዱ ፡ እንደማይለወጥ ፡ አብልጦ ፡ ሊያሳያቸው ፡ ስለ ፡ ፈቀደ ፥ እግዚአብሔር ፡ ሊዋሽ ፡ በማይቻል ፡ በሁለት ፡ በማይለወጥ ፡ ነገር ፥ በፊታችን ፡ ያለውን ፡ ተስፋ ፡ ለመያዝ ፡ ለሸሸን ፡ ለእኛ ፡ ብርቱ ፡ መጽናናት ፡ ይሆንልን ፡ ዘንድ ፥ በመሐላ ፡ በመካከል ፡ ገባ ፤ ፲፱ ይህም ፡ ተስፋ ፡ እንደ ፡ ነፍስ ፡ መልሕቅ ፡ አለን ፡ እርሱም ፡ አርግጥና ፡ ጽኑ ፡ የሆነ ፡ ወደ ፡ መጋረጃውም ፡ ውስጥ ፡ የገባ ፡ ነው ፤ ፳ በዚያም ፡ ኢየ

፭። ፫፤ ዘሌዋ. ፱፥፯ ። ፬፤ ዘፀአ. ፳፰፥፩ ። ፭፤ የሐ. ፰፥፶፬፤ መዝ. ፪፥፯ ። ፮፤ መዝ. ፻፲፥፬ ። ፯፤ ማር. ፲፬፥፴፭፡፴፮፤ ፲፭፥፴፬፤ ዮሐ. ፲፯፥፩፤ መዝ. ፳፪፥፳፬ ። ፰፤ ፊልጵ. ፪፥፰ ። ፱፤ ኢሳ. ፵፭፥፲፯ ። ፲፪፤ ፩ቆሮ. ፫፥፪ ።
፮። ፩፡፪፤ የሐዋ. ፲፱፥፬—፮፤ ፲፯፥፴፩፡፴፪፤ ፲፥፵፪ ። ፬፤ ገላ. ፫፥፬፤ ፭ ። ፮፤ ዮሐ. ፲፥፴፩፡፴፪ ። ፯፤ መዝ. ፷፭፥፲ ። ፰፤ ኢሳ. ፭፥፩—፯ ። ፲፤ ማቴ. ፲፥፵፪ ። ፲፩፤ ሮሜ. ፭፥፭ ። ፲፫፡፲፬፤ ዘፍጥ. ፳፪፥፲፮፡፲፯ ። ፲፮፤ ዘፀአ. ፳፪፥፲፩ ። ፲፯፤ ቲቶ ፩፥፪ ። ፲፱፤ ዘሌዋ. ፲፮፥፪ ። ፳፤ ዮ. ፭፥፮ ።

ሱስ ፡ እንደ ፡ መልከ ፡ ጼዴቅ ፡ ሹመት ፡ ለዘላ
ለም ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ የሆነው ፥ ስለ ፡ እኛ ፡
ቀዳሚ ፡ ሆኖ ፡ ገባ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ፡ የሳሌም ፡ ንጉሥና ፡ የልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡
ካህን ፡ የሆነ ፡ ይህ ፡ መልከ ፡ ጼዴቅ ፡ አብርሃም ፡
ነገሥታትን ፡ ገድሎ ፡ ሲመለስ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተገ
፪ ፡ ናኝቶ ፡ ባረከው ፤ ለእርሱም ፡ ደግሞ ፡ አብርሃም ፡
ከሁሉ ፡ አሥራትን ፡ አካፈለው ። የስሙም ፡
ትርጓሜ ፡ በመጀመሪያ ፡ የጽድቅ ፡ ንጉሥ ፡ ነው ፥
ኋላም ፡ ደግሞ ፡ የሳሌም ፡ ንጉሥ ፡ ማለት ፡ የሰ
፫ ፡ ላም ፡ ንጉሥ ፡ ነው ። አባትና ፡ እናት ፡ የትው
ልድም ፡ ቍጥር ፡ የሉትም ፥ ለዘመኑም ፡ ጥንት ፡
ለሕይወቱም ፡ ፍጻሜ ፡ የለውም ፥ ዳሩ ፡ ግን ፡
በእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ተመስሎ ፡ ለዘላለም ፡
ካህን ፡ ሆኖ ፡ ይኖራል ።

፬ ፡ የአባቶች ፡ አለቃ ፡ አብርሃም ፡ ከዘረፋው ፡
የሚሻለውን ፡ አሥራት ፡ የሰጠው ፡ ይህ ፡ ሰው ፡
እንዴት ፡ ታላቅ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ አስቡ ፡ ተመል
፭ ፡ ከቱ ። ከሌዊ ፡ ልጆችም ፡ ክህነትን ፡ የሚቀበ
ሉት ፡ ከሕዝቡ ፡ ማለት ፡ ከወንድሞቻቸው ፥ እነ
ርሱ ፡ ምንም ፡ ከአብርሃም ፡ ወገብ ፡ ቢወጡ ፥
ከእነርሱ ፡ አሥራትን ፡ በሕግ ፡ እንዲያስወጡ ፡
፮ ፡ ትእዛዝ ፡ አላቸው ፤ ትውልዱ ፡ ከእነርሱ ፡ የማ
ይቈጠረው ፡ ግን ፡ ከአብርሃም ፡ አሥራትን ፡ አው
ጥቶአል ፥ የተስፋ ፡ ቃል ፡ የነበረውንም ፡ ባርኮ
፯ ፡ አል ። ታናሹም ፡ በታላቁ ፡ እንዲባረክ ፡ ክርክር ፡
፰ ፡ የሌለበት ፡ ነገር ፡ ነው ። በዚህስ ፡ የሚሞቱ ፡
ሰዎች ፡ አሥራትን ፡ ያስወጣሉ ፥ በዚያ ፡ ግን ፡
የሚያስወጣ ፡ በሕይወት ፡ እንዲኖር ፡ የተመሰ
፱ ፡ ከረለት ፡ እርሱ ፡ ነው ። ይህንም ፡ ለማለት ፡ ሲፈ
ቀድ ፥ አሥራትን ፡ የሚያስወጣ ፡ ሌዊ ፡ እንኳ ፡
በአብርሃም ፡ እጅ ፡ አሥራትን ፡ ሰጥቶአል ፤
፲ ፡ መልከ ፡ ጼዴቅ ፡ በተገናኘው ፡ ጊዜ ፡ ገና ፡ በአ
ባቱ ፡ ወገብ ፡ ነበረና ።

፲፩ ፡ እንግዲህ ፡ ሕዝቡ ፡ በሌዊ ፡ ክህነት ፡ የተመሠ
ረተን ፡ ሕግ ፡ ተቀብለዋልና ፡ በዚያ ፡ ክህነት ፡
ፍጹምነት ፡ የተገኘ ፡ ቢሆን ፥ እንደ ፡ አሮን ፡
ሹመት ፡ የማይቈጠር ፥ እንደ ፡ መልከ ፡ ጼዴቅ ፡
ሹመት ፡ ግን ፡ የሆነ ፡ ሌላ ፡ ካህን ፡ ሊነሣ ፡ ወደ ፡
፲፪ ፡ ፊት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ያስፈልጋል ? ክህነቱ ፡ ሲለ
ወጥ ፥ ሕጉ ፡ ደግሞ ፡ ሊለወጥ ፡ የግድ ፡ ነውና ።
፲፫ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ የተነገረለት ፡ እርሱ ፡ በሌላ ፡ወገን ፡
ተካፍሎአልና ፥ ከዚያም ፡ መሠዊያውን ፡ ያገለ
፲፬ ፡ ገለ ፡ ማንም ፡ የለም ፤ ጌታችን ፡ ከይሁዳ ፡ ነገድ ፡
እንደ ፡ ወጣ ፡ የተገለጠ ፡ ነውና ፥ ስለዚህም ፡
ነገድ ፡ ሙሴ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ስለ ፡ ክህነት ፡ አል
ተናገረም ።

፲፭፡፲፮ ፡ በማያልፍም ፡ ሕይወት ፡ ኃይል ፡ እንጂ ፡ በሥጋ ፡
ትእዛዝ ፡ ሕግ ፡ ሳይሆን ፡ ሌላ ፡ ካህን ፡ በመልከ ፡
ጼዴቅ ፡ ምሳሌ ፡ ቢነሣ ፥ ይህ ፡ እጅግ ፡ አብልጦ ፡
፲፯ ፡ የሚገለጥ ፡ ነው ። አንተ ፡ እንደ ፡ መልከ ፡ ጼዴቅ ፡
ሹመት ፡ ለዘላለም ፡ ካህን ፡ ነህ ፡ ብሎ ፡ ይመሰክ
፲፰፡፲፱ ፡ ራልና ። ሕጉ ፡ ምንም ፡ ፍጹም ፡ አላደረገምና ፥
ስለዚህም ፡ የምትደክም ፡ የማትጠቅምም ፡ ስለ ፡
ሆነች ፡ የቀደመች ፡ ትእዛዝ ፡ ተሽራለች ፥ ወደ ፡
እግዚአብሔርም ፡ የምንቀርብበት ፡ የሚሻል ፡
ተስፋ ፡ ገብቶአል ።

፳፡፳፩ ፡ እነርሱም ፡ ያለ ፡ መሐላ ፡ ካህናት ፡ ሆነዋልና ፤
እርሱ ፡ ግን ፡— ጌታ ፡— አንተ ፡ እንደ ፡ መልከ ፡
ጼዴቅ ፡ ሹመት ፡ ለዘላለም ፡ ካህን ፡ ነህ ፡ ብሎ ፡
ማለ ፡ አይጸጸትም ፡ ብሎ ፡ በተናገረለት ፡ ከመ
ሐላ ፡ ጋር ፡ ካህን ፡ ሆኖአልና ፡ ያለ ፡ መሐላ ፡
፳፪ ፡ ካህን ፡ እንዳልሆነ ፡ መጠን ፥ እንዲሁ ፡ ኢየሱስ ፡
ለሚሻል ፡ ኪዳን ፡ ዋስ ፡ ሆኖአል ።

፳፫ ፡ እነርሱም ፡ እንዳይኖሩ ፡ ሞት ፡ ስለ ፡ ከለከላ
፳፬ ፡ ቸው ፡ ካህናት ፡ የሆኑት ፡ ብዙ ፡ ናቸው ፤ እርሱ ፡
ግን ፡ ለዘላለም ፡ የሚኖር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የማይለ
፳፭ ፡ ወጥ ፡ ክህነት ፡ አለው ፤ ስለ ፡ እነርሱም ፡ ሊያ
ማልድ ፡ ዘወትር ፡ በሕይወት ፡ ይኖራልና ፡ ስለ
ዚህ ፡ ደግሞ ፡ በእርሱ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
የሚመጡትን ፡ ፈጽሞ ፡ ሊያድናቸው ፡ ይችላል ።

፳፮ ፡ ቅዱስና ፡ ያለ ፡ ተንኰል ፡ ነውርም ፡ የሌለበት ፡
ከኃጢአተኞችም ፡ የተለየ ፡ ከሰማያትም ፡ ከፍ ፡
ከፍ ፡ ያለ ፥ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ ይገ
፳፯ ፡ ባናል ፤ እርሱም ፡ እንደነዚያ ፡ ሊቃነ ፡ ካህናት ፡
አስቀድሞ ፡ ስለ ፡ ራሱ ፡ ኃጢአት ፡ በኋላም ፡
ስለ ፡ ሕዝቡ ፡ ኃጢአት ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ መሥዋ
ዕትን ፡ ሊያቀርብ ፡ አያስፈልገውም ፤ ራሱን ፡
ባቀረበ ፡ ጊዜ ፡ ይህን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ፈጽሞ ፡ አድ
፳፰ ፡ ርጎአልና ። ሕጉ ፡ ድካም ፡ ያላቸውን ፡ ሰዎች ፡
ሊቀ ፡ ካህናት ፡ አድርጎ ፡ ይሾማልና ፤ ከሕግ ፡
በኋላ ፡ የመጣ ፡ የመሐላው ፡ ቃል ፡ ግን ፡ ለዘላ
ለም ፡ ፍጹም ፡ የሆነውን ፡ ልጅ ፡ ይሾማል ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ ፡ ከተናገርነውም ፡ ዋና ፡ ነገሩ ፡ ይህ ፡ ነው ፤
በሰማያት ፡ በግርማው ፡ ዙፋን ፡ ቀኝ ፡ የተቀመጠ ፡
፪ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ አለን ፤ እርሱም ፡
የመቅደስና ፡ የእውነተኛይቱ ፡ ድንኳን ፡ አገል
ጋይ ፡ ነው ፥ እርስዋም ፡ በሰው ፡ ሳይሆን ፡ በጌታ ፡
፫ ፡ የተተከለች ፡ ናት ። ሊቀ ፡ ካህናት ፡ ሁሉ ፡ መባ
ንና ፡ መሥዋዕትን ፡ ሊያቀርብ ፡ ይሾማልና ፤ ስለ
ዚህም ፡ ለዚህ ፡ ደግሞ ፡ የሚያቀርበው ፡ እን
፬ ፡ ዳች ፡ ሊኖረው ፡ የግድ ፡ ነው ። እንግዲህ ፡ በም
ድር ፡ ቢኖርስ ፥ እንደ ፡ ሕግ ፡ መባን ፡ የሚያቀር
፭ ፡ ቡት ፡ ስላሉ ፥ ካህን ፡ እንኳ ፡ ባልሆነም ፤ እነር
ሱም ፡ ሙሴ ፡ ድንኳኒቱን ፡ ሊሠራ ፡ ሳለ ፡
እንደ ፡ ተረዳ ፥ ለሰማያዊ ፡ ነገር ፡ ምሳሌና ፡ ጥላ ፡

፯ ። ፩—፲ ፤ ዘፍጥ. ፲፬ ፥ ፲፰—፳ ። ፭ ፤ ዘኍል. ፲፰ ፥ ፳፩ ። ፲፩ ፤ ገላ. ፪ ፥ ፳፩ ፤ መዝ. ፻፲ ፥ ፬ ። ፲፬ ፤ ዘፍጥ. ፵፱ ፥ ፲ ፤
ኢሳ. ፲፩ ፥ ፩ ፤ ሚክ. ፭ ፥ ፪ ። ፲፯ ፤ ም. ፭ ፥ ፮ ። ፳፩ ፤ ቍ. ፲፯ ። ፳፭ ፤ ሮሐ. ፲፬ ፥ ፮ ፤ ሮሜ. ፰ ፥ ፴፬ ። ፳፯ ፤ ም.
፱ ፥ ፲፪ ፥ ፳፰ ። ፳፰ ፤ ዘሌዋ. ፲፮ ፥ ፮ ፥ ፲፭ ፤ ሮሜ. ፮ ፥ ፲ ። ፳፰ ፤ ም. ፭ ፥ ፩ ፥ ፪ ።
፰ ። ፩ ፤ መዝ. ፻፲ ፥ ፩ ። ፫ ፤ ም. ፭ ፥ ፩ ፤ ኤፌ. ፭ ፥ ፪ ። ፭ ፤ ዘፀአ. ፳፭ ፥ ፵ ።

የሚሆነውን፡ያገለግላሉ ። በተራራው፡ እንደ፡ ተገለጠልህ፡ ምሳሌ፡ሁሉን፡ ታደርግ፡ ዘንድ፡ ተጠንቀቅ፡ብሎት፡ነበርና ። ፮ አሁን፡ግን፡በሚሻል፡ ተስፋ፡ ቃል፡ በተመሠረተ፡ በሚሻል፡ ኪዳን፡ደግሞ፡መካከለኛ፡እንደሚሆን÷በዚያ፡ልክ፡ እጅግ፡ የሚሻል፡ አገልግሎት፡ አግኝቶአል ። ፯ ፊተኛው፡ ኪዳን፡ ነቀፋ፡ ባይኖረው÷ ለሁለተኛው፡ስፍራ፡ባልተፈለገም፡ነበር ።

፰ እነርሱን፡ እየነቀፈ፡ ይላቸዋልና፡—

እነሆ÷ከእስራኤል፡ቤትና፡ከይሁዳ፡ቤት፡ ጋር፡ አዲስ፡ኪዳን፡ የምገባበት፡ ወራት፡ ይመጣል፡ ይላል፡ ጌታ ፤ ፱ ከግብፅ፡ አገር፡ አወጣቸው፡ ዘንድ፡ እጃቸውን፡ በያዝሁበት፡ ቀን፡ ከአባቶቻቸው፡ ጋር፡ እንደገባሁት፡ ኪዳን፡ አይደለም ፤ እነርሱ፡ በኪዳኔ፡ አልጸኑምና÷ እኔም፡ ቸል፡ አልኋቸው፡ይላል፡ጌታ ። ፲ ከዚያ፡ወራት፡በኋላ፡ ከእስራኤል፡ቤት፡ ጋር፡የምገባው፡ ቃል፡ ኪዳን፡ይህ፡ነውና፡ ይላል፡ጌታ ፤ ሕጌን፡ በልቡናቸው፡ አኖራለሁ፡ በልባቸውም፡ እጽፈዋለሁ÷እኔም፡ አምላክ፡ እሆንላቸዋለሁ፡ እነርሱም፡ ሕዝብ፡ይሆኑልኛል ። ፲፩ እያንዳንዱም፡ ጕረቤቱን፡እያንዳንዱም፡ ወንድሙን፡—ጌታን፡ እወቅ፡ ብሎ፡ አያስተምርም÷ከታናናሽ፡ጀምሮ፡እስከ፡ታላቁ፡ ድረስ፡ ሁሉ፡ ያውቁኛልና ። ፲፪ ዓመፃቸውን፡ እምራቸዋለሁና÷ ኃጢአታቸውንም፡ ደግሜ፡ አላስብም ።

፲፫ አዲስ፡ በማለቱ፡ ፊተኛውን፡ አስረጅቶአል ፤ አርጌና፡ ውራጅ፡ የሆነውስ፡ ሊጠፋ፡ ቀርቦአል ።

ምዕራፍ፡ ፱ ።

፩ ፊተኛይቱም፡ ደግሞ፡ የአገልግሎት፡ሥርዓትና፡ የዚህ፡ ዓለም፡ የሆነው፡ መቅደስ፡ ነበራት ። ፪ የመጀመሪያይቱ፡ድንኳን፡ ተዘጋጅታ፡ ነበርና÷ በእርስዋም፡ ቅድስት፡ በምትባለው፡ ውስጥ፡ መቅረዙና፡ ጠረጴዛው፡ የመሥዋዕቱም፡ ኅብስት፡ ነበረበት ፤ ፫ ከሁለተኛውም፡ መጋረጃ፡ ወዲያ፡ ቅድስተ፡ ቅዱሳን፡ የምትባለው፡ ድንኳን፡ ነበረች÷ ፬ በዚያም፡ ውስጥ፡ የወርቅ፡ማዕጠንት፡ነበረ፡ሁለንተናዋም፡በወርቅ፡ የተለበጠች፡ የኪዳን፡ ታቦት ፤ በእርስዋም፡ውስጥ፡መና፡ያለበት፡የወርቅ፡መሶብና፡ የበቀለች፡ የአሮን፡በትር፡ የኪዳኑም፡ ጽላት፡ ፭ ነበሩ÷ በላይዋም፡ማስተስረያውን፡የሚጋርዱ፡ የክብር፡ ኪሩቤል፡ነበሩ ፤ ስለ፡ እነዚህም፡ ስለ፡ እያንዳንዳቸው፡ ልንናገር፡ አሁን፡ አንችልም ።

፮ ይህም፡እንደዚህ፡ ተዘጋጅቶ፡ ሳለ÷ ካህናት፡ አገልግሎታቸውን፡እየፈጸሙ፡ዘወትር፡በፊተኛይቱ፡ ድንኳን፡ ይገቡባታል ፤ ፯ በሁለተኛይቱ፡ ግን፡ሊቀ፡ካህናት፡ብቻውን፡ በዓመት፡ አንድ፡ ጊዜ፡ ይገባባታል÷ እርሱም፡ ስለ፡ ራሱና፡ ስለ፡ ሕዝቡ፡ስሕተት፡የሚያቀርበውን፡ ደም፡ ሳይዝ፡ አይገባም ፤ ፰ ፊተኛይቱም፡ ድንኳን፡ በዚህ፡ገና፡ ቆማ፡ ሳለች÷ ወደ፡ ቅድስት፡ የሚወስደው፡ መንገድ፡ገና፡ እንዳልተገለጠ፡መንፈስ፡ቅዱስ፡ ያሳያል ። ፱ ይህም፡ ለአሁኑ፡ ጊዜ፡ ምሳሌ፡ ነው÷ እንደዚህም፡ መባና፡ መሥዋዕት፡ ይቀርባሉ ፤ እነዚህም፡ እስከ፡ መታደስ፡ ዘመን፡ ድረስ፡የተደረጉ÷ ስለ፡ ምግብና፡ ስለ፡ መጠጥም፡ ስለ፡ ልዩ፡ ልዩ፡ መታጠብም፡ የሚሆኑ፡ የሥጋ፡ ሥርዓቶች፡ ብቻ፡ ናቸውና፡ የሚያመልከውን፡ በሕሊና፡ ፍጹም፡ ሊያደርጉት፡ አይችሉም ።

፲፩ ነገር፡ግን፡ ክርስቶስ፡ ይመጣ፡ ዘንድ፡ ላለው፡ መልካም፡ ነገር፡ ሊቀ፡ ካህናት፡ ሆኖ÷በምትበልጠውና፡ በምትሻለው፡ በእጆችም፡ ባልተሠራች፡ ማለት፡ ለዚህ፡ ፍጥረት፡ ባልሆነች፡ ድንኳን÷ ፲፪ የዘላለምን፡ቤዛነት፡አግኝቶ፡አንድ፡ ጊዜ፡ ፈጽሞ፡ ወደ፡ ቅድስት፡ በገዛ፡ ደሙ፡ ገባ፡ እንጂ፡ በፍየሎችና፡ በጥጆች፡ ደም፡ አይደለም ። ፲፫ የኮርማዎችና፡ የፍየሎች፡ ደም፡ በረከሱትም፡ ላይ፡ የተረጨ፡ የጊደር፡ አመድ፡ ሥጋን፡ ለማንጻት፡ የሚቀድሱ፡ ከሆኑ÷ ፲፬ ነውር፡ የሌለው፡ ሆኖ፡ በዘላለም፡ መንፈስ፡ ራሱን፡ ለእግዚአብሔር፡ ያቀረበ፡ የክርስቶስ፡ ደም፡ እንዴት፡ ይልቅ፡ ሕያውን፡እግዚአብሔርን፡ልታመልኩ፡ከሞተ፡ ሥራ፡ ሕሊናችሁን፡ ያነጻ፡ ይሆን ?

፲፭ ስለዚህም፡ የፊተኛው፡ ኪዳን፡ ሲጸና፡ ሕግን፡ የተላለፉትን፡ የሚቤዥ፡ ሞት፡ ስለ፡ ሆነ÷ የተጠሩት፡ የዘላለምን፡ ርስት፡ የተስፋ፡ ቃል፡ እንዲቀበሉ፡ እርሱ፡ የአዲስ፡ ኪዳን፡ መካከለኛ፡ ነው ። ፲፮ ኑዛዜ፡ ያለ፡ እንደ፡ ሆነ፡ የተናዘዘው፡ ሞት፡ ማርዳት፡ የግድ፡ ነውና ፤ ፲፯ ሰው፡ ሲሞት፡ ኑዛዜው፡ ይጸናልና÷ ተናዛዡ፡ በሕይወት፡ ሲኖር፡ ግን፡ ከቶ፡ አይጠቅምም ። ፲፰ ስለዚህም፡ ፊተኛው፡ ኪዳን፡ እንኳ፡ ያለ፡ ደም፡ አልተመረቀም ። ፲፱ ሙሴም፡ ትእዛዛትን፡ ሁሉ፡ እንደ፡ ሕጉ፡ ለሕዝቡ፡ ሁሉ፡ ከተናገረ፡ በኋላ÷ የጥጆችንና፡ የፍየሎችን፡ ደም፡ ከውኃና፡ ከቀይ፡ የበግ፡ ጠጕር፡ ከሂሶጵም፡ ጋር፡ ይዞ፡— እግዚአብሔር፡ ያዘዛችሁ፡ የኪዳን፡ ደም፡ ይህ፡ ነው፡ ብሎ፡ በመጽሐፉና፡ በሕዝቡ፡ ሁሉ፡ ላይ፡ ረጨው ። ፳፩ እንዲሁም፡ በድንኳኒቱና፡ በማገልገያው፡ ዕቃ፡ ሁሉ፡ ደምን፡ ረጨ ። ፳፪ እንደ፡ ሕጉም፡ ከጥቂቶች፡ በቀር፡ ነገር፡ ሁሉ፡ በደም፡ ይነጻል÷

---

፰። [illegible]

፱። [illegible]

ደምም፡ሳይፈስ፡ስርየት፡የለም ።

፳፫ እንግዲህ፡በሰማያት፡ያሉትን፡የሚመስ ሰው፡ነገር፡በዚህ፡ሊነጻ፡እንጂ፡በሰማያት፡ ያሉቱ፡ራሳቸው፡ከእርሱ፡ይልቅ፡በሚበልጥ፡ መሥዋዕት፡ሊነጹ፡የግድ፡ነበረ ።

፳፬ ክርስቶስ፡ በእጅ፡ወደ፡ተሠራች÷የእውነተኛይቱ፡ምሳሌ፡ ወደምትሆን፡ቅድስት፡አልገባምና÷ነገር፡ ግን፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡ስለ፡እኛ፡አሁን፡ ይታይ፡ዘንድ፡ወደ፡እርስዋ፡ወደ፡ሰማይ፡ ገባ ።

፳፭ ሊቀ፡ካህናትም፡በየዓመቱ፡የሌላውን፡ ደም፡ይዞ፡ወደ፡ቅድስት፡እንደሚገባ÷ራሱን፡ ብዙ፡ጊዜ፡ሊያቀርብ፡አልገባም ፤

፳፮ እንዲህ፡ ቢሆንስ÷ዓለም፡ከተፈጠረ፡ጀምሮ፡ብዙ፡ጊዜ፡ መከራ፡ሊቀበል፡በተፈለገው፡ነበር ፤ አሁን፡ ግን፡በዓለም፡ፍጻሜ፡ራሱን፡በመሠዋት፡ ኀጢአትን፡ሊሽር፡አንድ፡ጊዜ፡ተገልጦአል ።

፳፯ ለሰዎችም፡አንድ፡ጊዜ፡መሞት፡ከእርሱ፡

፳፰ በኋላም፡ፍርድ፡እንደ፡ተመደበባቸው÷እን ዲሁ፡ክርስቶስ፡ደግሞ÷የብዙዎችን፡ኀጢ አት፡ሊሸከም፡አንድ፡ጊዜ፡ከተሠዋ፡በኋላ÷ ያድናቸው፡ዘንድ፡ለሚጠባበቁት፡ሁለተኛ፡ ጊዜ፡ያለ፡ኀጢአት፡ይታይላቸዋል ።

## ምዕራፍ፡ ፲ ።

፩ ሕጉ፡ሊመጣ፡ያለው፡የበጎ፡ነገር፡እውነተኛ፡ አምሳል፡ሳይሆን፡የነገር፡ጥላ፡አለውና÷ስለ ዚህም፡በየዓመቱ፡ዘወትር፡በሚያቀርቡት፡ በዚያ፡መሥዋዕት፡የሚቀርቡትን፡ሊፈጽም፡

፪ ከቶ፡አይችልም ። እንደዚህማ፡ባይሆን÷የሚ ያመልኩት፡አንድ፡ጊዜ፡ነጽተው፡ከዚያ፡በኋላ፡ በሕሊናቸው፡ኀጢአትን፡ስላላወቁ፡ማቅረ

፫ ብን፡በተዉ፡አልነበረምን ? ነገር፡ግን፡በዚያ፡ መሥዋዕት፡በየዓመቱ፡የኀጢአት፡መታሰቢያ፡

፬ አለ ፤ የኮርማዎችና፡የፍየሎች፡ደም፡ኀጢአ ትን፡እንዲያስወግድ፡የማይቻል፡ነውና ።

፭ ስለዚህ፡ወደ፡ዓለም፡ሲገባ፡—

መሥዋዕትንና፡መባን፡አልወደድህም፡

፮ ሥጋን፡ግን፡አዘጋጀህልኝ ፤ በሙሉ፡በሚ ቃጠል፡መሥዋዕትና፡ስለ፡ኀጢአት፡ ስሚሠዋ፡መሥዋዕት፡ደስ፡አላሰህም ።

፯ በዚያን፡ጊዜ፡— እነሆ÷በመጽሐፍ፡ጥቅ ልል፡ስለ፡እኔ፡እንደ፡ተጻፈ÷አምላኬ፡ ሆይ÷ፈቃድህን፡ላደርግ፡መጥቼአለሁ፡ አልሁ፡

፰ ይላል ። በዚህ፡ላይ፡— መሥዋዕትንና፡መባን፡ ስሙሉ፡የሚቃጠል፡መሥዋዕትንም፡ስለ፡ ኀጢአትም፡የሚሠዋ፡መሥዋዕትን፡አልወደ ድህም፡በእርሱም፡ደስ፡አላለህም፡ብሎ÷እነ ዚህም፡እንደ፡ሕግ፡የሚቀርቡት፡ናቸው÷

፱ ቀጥሎ፡— እነሆ÷አምላኬ፡ሆይ÷ፈቃድህን፡ ላደርግ፡መጥቼአለሁ፡ብሎአል ። ሁለተኛ

፲ ውን፡ሊያቆም፡የፊተኛውን፡ይሽራል ። በዚ ህም፡ፈቃድ፡የኢየሱስ፡ክርስቶስን፡ሥጋ፡ አንድ፡ጊዜ፡ፈጽሞ፡በማቅረብ፡ተቀድሰናል ።

፲፩ ሊቀ፡ካህናትም፡ሁሉ፡ዕለት፡ዕለት፡እያገ ለገለ፡ኀጢአትን፡ሊያስወግዱ፡ከቶ፡የማይች ሉትን፡እነዚያን፡መሥዋዕቶች፡ብዙ፡ጊዜ፡

፲፪ እያቀረበ፡ቆሞአል ፤ እርሱ፡ግን፡ስለ፡ኀጢ አት፡አንድን፡መሥዋዕት፡ለዘላለም፡አቅርቦ፡

፲፫ በእግዚአብሔር፡ቀኝ፡ተቀመጠ÷ጠላቶቹም፡ የእግሩ፡መረገጫ፡እስኪደረጉ፡ድረስ፡ወደ፡

፲፬ ፊት፡ይጠብቃል ። አንድ፡ጊዜ፡በማቅረብ፡ የሚቀደሱትን፡የዘላለም፡ፍጹማን፡አድርጎአ

፲፭፡፲፮ ቸዋልና ። መንፈስ፡ቅዱስም፡ደግሞ፡ስለዚህ፡ ይመሰክርልናል ፤

ከዚያ፡ወራት፡በኋላ፡ከእነርሱ፡ጋር፡የም ገባው፡ኪዳን፡ይህ፡ነው፡ይላል፡ጌታ ፤ በልባቸው፡ሕጌን፡አኖራለሁ፡በልቡናቸ ውም፡እጽፈዋለሁ፡

፲፯ ብሎ፡ከተናገረ፡በኋላ÷ኀጢአታቸውንና፡ዓመ

፲፰ ፃቸውንም፡ደግሜ፡አላስብም፡ይላል ። የእነዚ ህም፡ስርየት፡ባለበት፡ዘንድ÷ከዚህ፡ወዲህ፡ ስለ፡ኀጢአት፡ማቅረብ፡የለም ።

፲፱፡፳ እንግዲህ÷ወንድሞች፡ሆይ÷በመረቀልን፡ በአዲስና፡በሕያው፡መንገድ፡ወደ፡ቅድስት፡ በኢየሱስ፡ደም፡በመጋረጃው፡ማለት፡በሥ ጋው፡በኩል፡እንድንገባ፡ድፍረት፡ስላለን÷

፳፩ በእግዚአብሔርም፡ቤት፡ላይ፡የሆነ፡ታላቅ፡

፳፪ ካህን፡ስላለን÷ከክፉ፡ሕሊና፡ለመንጻት፡ልባ ችንን፡ተረጭተን፡ሰውነታችንንም፡በጥሩ፡ ውኃ፡ታጥበን፡በተረዳንበት፡እምነት፡በቅን፡

፳፫ ልብ፡እንቅረብ ፤ የተስፋን፡ቃል፡የሰጠው፡ የታመነ፡ነውና፡እንዳይነቃነቅ፡የተስፋችንን፡

፳፬ ምስክርነት፡እንጠብቅ ፤ ለፍቅርና፡ለመልካ ምም፡ሥራ፡እንድንነቃቃ፡እርስ፡በርሳችን፡

፳፭ እንተያይ ፤ በአንዳንዶችም፡ዘንድ፡ልማድ፡ እንደ፡ሆነው÷መሰብሰባችንን፡አንተው፡እርስ፡ በርሳችን፡እንመካከር፡እንጂ ፤ ይልቁንም፡ቀኑ፡ ሲቀርብ፡እያያችሁ፡አብልጣችሁ፡ይህን፡አድ ርጉ ።

፳፮ የእውነትን፡እውቀት፡ከተቀበልን፡በኋላ፡ ወደን፡ኀጢአት፡ብናደርግ፡ከእንግዲህ፡ወዲህ፡ ስለ፡ኀጢአት፡መሥዋዕት፡አይቀርልንምና÷

፳፯ የሚያስፈራ፡ግን፡የፍርድ፡መጠበቅ፡ተቃዋ ሚዎችንም፡ሊበላ፡ያለው፡የእሳት፡ብርታት፡

፳፰ አለ ። የሙሴን፡ሕግ፡የናቀ፡ሰው፡ሁለት፡ ወይም፡ሦስት፡ቢመሰክሩበት፡ያለ፡ርኅራኄ፡

፳፱ ይሞታል ፤ የእግዚአብሔርን፡ልጅ፡የረገጠ፡

፱። ፳፬፡ ሮሜ፡ [illegible] ። ፳፰፡ ኢሳ፡ [illegible]፡ ፊልጵ፡ [illegible] ።

፲። [illegible]

ያንንም ፡ የተቀደሰበትን ፡ የኪዳኑን ፡ ደም ፡ እንደ ፡ ርኩስ ፡ ነገር ፡ የቈጠረ ፡ የጸጋውንም ፡ መንፈስ ፡ ያክፋፋ ÷ እንዴት ፡ ይልቅ ፡ የሚብስ ፡ ቅጣት ፡ የሚገባው ፡ ይመስላችኋል ? ፴፤ በቀል ፡ የእኔ ፡ ነው ÷ እኔ ፡ ብድራትን ፡ እመልሳለሁ ፡ ያለውን ፡ እናውቃለንና ፤ ደግሞም ፡— ጌታ ፡ በሕዝቡ ፡ ፴፩፤ ይፈርዳል ። ሕያው ፡ እግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ መውደቅ ፡ የሚያስፈራ ፡ ነው ።

፴፪፣፴፫፤ ነገር ፡ ግን ፡ ግማሽ ፡ በነቀፋና ፡ በጭንቀ ፡ እንደ ፡ መጫወቻ ፡ ስለ ፡ ሆናችሁ ፡ ግማሽም ፡ እንዲህ ፡ ካሉት ፡ ጋር ፡ ስለ ፡ ተካፈላችሁ ÷ ብርሃን ፡ ከበራላችሁ ፡ በኋላ ፡ መከራ ፡ በሆነበት ፡ በትልቅ ፡ ተጋድሎ ፡ የጸናችሁበትን ፡ የቀደመውን ፡ ዘመን ፡ ፴፬፤ አስቡ ። የሚበልጥና ፡ ለዘወትር ፡ የሚኖር ፡ ገንዘብ ፡ በሰማይ ፡ ራሳችሁ ፡ እንዳላችሁ ፡ አውቃችሁ ÷ በእስራቴ ፡ ራራችሁልኝ ፡ የገንዘባችሁንም ፡ ንጥቂያ ፡ በደስታ ፡ ተቀበላችሁ ። ፴፭፤ እንግዲህ ፡ ታላቅ ፡ ብድራት ፡ ያለውን ፡ ድፍረታችሁን ፡ ፴፮፤ አትጣሉ ። የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ አድርጋችሁ ፡ የተስጣችሁን ፡ የተስፋ ፡ ቃል ፡ እንድታገኙ ፡ መጽናት ፡ ያስፈልጋችኋልና ።

፴፯፤ ገና ፡ በጣም ፡ ጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ነው ÷ ሊመጣ ፡ ያለ ፡
፴፰፤ ውም ፡ ይመጣል ፡ አይዘገይምም ፤ ጻድቅ ፡
ግን ፡ በእምነት ፡ ይኖራል ፡ ወደ ፡ ኋላም ፡
ቢያፈገፍግ ÷ ነፍሴ ፡ በእርሱ ፡ ደስ ፡ አይላ
ትም ።

፴፱፤ እኛ ፡ ግን ፡ ነፍሳችውን ፡ ሊያድኑ ፡ ከሚያምኑቱ ፡ ነን ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ ከሚያፈገፍጉ ፡ አይደለንም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

፩፤ እምነትም ፡ ተስፋ ፡ ስለምናደርገው ፡ ነገር ፡ የሚያስረግጥ ፤ የማናየውንም ፡ ነገር ፡ የሚያስ ፪፤ ረዳ ፡ ነው ። ለሽማግሌዎች ፡ የተመሰከረላቸው ፡ ፫፤ በዚህ ፡ ነውና ። ዓለሞች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንደ ፡ ተዘጋጁ ÷ ስለዚህም ፡ የሚታየው ፡ ነገር ፡ ከሚታዩት ፡ እንዳልሆነ ፡ በእምነት ፡ እናስተውላለን ።

፬፤ አቤል ፡ ከቃየል ፡ ይልቅ ፡ የሚበልጥን ፡ መሥዋዕት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በእምነት ፡ አቀረበ ÷ በዚህም ÷ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ስጦታው ፡ ሲመሰክር ÷ እርሱ ፡ ጻድቅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ተመሰከረለት ፤ ሞቶም ፡ ሳለ ፡ በመሥዋዕቱ ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ ፭፤ ይናገራል ። ሄኖክ ፡ ሞትን ፡ እንዳያይ ፡ በእምነት ፡ ተወሰደ ÷ እግዚአብሔርም ፡ ስለ ፡ ወሰደው ፡ አልተገኘም ። ሳይወሰድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፮፤ ደስ ፡ እንዳሰኘ ፡ ተመስክሮለታልና ፤ ያለ ፡ እምነትም ፡ ደስ ፡ ማሰኘት ፡ አይቻልም ፤ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚደርስ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳለ ፡ ለሚፈልጉትም ፡ ዋጋ ፡ እንዲሰጥ ፡ ያምን ፡ ዘንድ ፡ ፯፤ ያስፈልገዋልና ። ኖኅ ፡ ገና ፡ ስለማይታየው ፡ ነገር ፡ ተረድቶ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እየፈራ ፡ ቤተ ፡ ሰዎቹን ፡ ለማዳን ፡ መርከብን ፡ በእምነት ፡ አዘጋጀ ÷ በዚህም ፡ ዓለምን ፡ ኰነነ ÷ በእምነትም ፡ የሚገኘውን ፡ ጽድቅ ፡ ወራሽ ፡ ሆነ ።

፰፤ አብርሃም ፡ የተባለው ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ ሊቀበለው ፡ ወዳለው ፡ ስፍራ ፡ ለመውጣት ፡ በእምነት ፡ ታዘዘ ÷ ወዴትም ፡ እንደሚሄድ ፡ ሳያውቅ ፡ ፱፤ ወጣ ። ለእንግዶች ፡ እንደሚሆን ፡ በተስፋ ፡ ቃል ፡ በተሰጠው ፡ አገር ፡ በድንኳን ፡ኖሮ ÷ ያን ፡ የተስፋ ፡ ቃል ፡ አብረውት ፡ ከሚወርሱ ፡ ከይስሐቅና ፡ ከያዕቆብ ፡ ጋር ÷ እንደ ፡ መጻተኛ ፡ በእ ፲፤ ምነት ፡ ተቀማጠ ፤ መሠረት ፡ ያላትን ÷ እግዚአብሔር ፡ የሠራትንና ፡ የፈጠራትን ፡ ከተማ ፡ ፲፩፤ ይጠብቅ ፡ ነበርና ። ተስፋ ፡ የሰጠው ፡ የታመነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ስለ ፡ ቈጠረች ÷ ሣራ ፡ ራስዋ ፡ ደግሞ ፡ ዕድሜዋ ፡ እንኳ ፡ ካለፈ ፡ በኋላ ፡ ዘርን ፡ ለመፅነስ ፡ ኃይልን ፡ በእምነት ፡ አገኘች ። ፲፪፤ ስለዚህ ፡ ደግሞ ፡ በብዛታቸው ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከዋክብ ፡ እንደማይቈጠርም ፡ በባሕር ፡ ዳር ፡ እንዳለ ፡ አሸዋ ፡ የነበሩት ፡ የሞተን ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ ከመሰለው ፡ ከአንዱ ፡ ተወለዱ ።

፲፫፤ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ አምነው ፡ ሞቱ ÷ የተሰጣቸውን ፡ የተስፋ ፡ ቃል ፡ አላገኙምና ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ ከሩቅ ፡ ሆነው ፡ አዩትና ፡ ተሳለሙት ÷ በምድርም ፡ እንግዶችና ፡ መጻተኞች ፡ እንዲሆኑ ፡ ፲፬፤ ታመኑ ። እንዲህ ፡ የሚሉት ፡ ለእነርሱ ፡ የሚሆነውን ፡ አገር ፡ እንዲፈልጉ ፡ ያመለክታሉና ። ፲፭፤ ያን ፡ የወጡበትን ፡ አገር ፡ አስበው ፡ ቢሆኑ ÷ ፲፮፤ ሊመለሱ ፡ ጊዜ ፡ በሆነላቸው ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ ግን ፡ የሚበልጠውን ፡ እርሱም ፡ ሰማያዊ ፡ አገር ፡ ይናፍቃሉ ። ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካቸው ፡ ተብሎ ፡ ሊጠራ ፡ በእነርሱ ፡ አያፍርም ÷ ከተማን ፡ አዘጋጅቶላቸዋልና ።

፲፯፣፲፰፤ አብርሃም ፡ በተፈተነበት ፡ ጊዜ ፡ ይስሐቅን ፡ በእምነት ፡ አቀረበ ÷ የተስፋን ፡ ቃል ፡ የተቀበለው ፡— በይስሐቅ ፡ ዘር ፡ ይጠራልሃል ፡ የተባለለት ፡ እርሱም ፡ አንድ ፡ ልጁን ፡ አቀረበ ፤ ፲፱፤ እግዚአብሔር ፡ ከሙታን ፡ እንኳ ፡ ሊያስነሣው ፡ እንዲቻለው ፡ አስቦአልና ÷ ከዚያም ፡ ደግሞ ፡ በምሳሌ ፡ አገኘው ። ፳፤ ይስሐቅ ፡ ሊመጣ ፡ ስላለው ፡ ነገር ፡ ያዕቆብንና ፡ ዔሳውን ፡ በእምነት ፡ ባረካቸው ። ፳፩፤ ያዕቆብ ፡ ሲሞት ፡ በእምነት ፡ የዮሴፍን ፡ ልጆች ፡ እያንዳንዳቸውን ፡ ባረካቸው ÷ በዘንጉም ፡

፲። ፴፤ ዘዳግ. ፴፪÷፴፭፣፴፮ ። ፴፪፤ ፊልጵ. ፩÷፳፱፣፴ ። ፴፬፤ ማቴ. ፭÷፲፪፤፩ ጴጥ. ፩÷፬ ። ፴፮፤ ሉቃ. ፳፩÷፲፱ ። ፴፯፣፴፰፤ ሐጌ ፪÷፯፤ እንባ. ፪÷፫፣፬ ።

፲፩። ፩፤ ሮሜ ፰÷፳፬ ። ፫፤ ዘፍጥ. ፩፤ ሮሜ ፬÷፲፯ ። ፬፤ ዘፍጥ. ፬÷፬—፰፤ ፲ ። ፭፤ ዘፍጥ. ፭÷፳፬—፳፬ ። ፯፤ ኤር. ፳፱÷፲፱—፲፱ ። ፰፤ ዘፍጥ. ፲፪÷፩፤ ፬፤ ፲፫—፳፱፤ ሮሜ ፬÷፲፫ ። ፱፤ ፲፤ ዘፍጥ. ፲፱÷፩—፰፤ ፴፭÷፳፯ ። ፲፤ ምዕ. ፲፫÷፲፬፤ ራእ. ፳፩÷፪፣፲፱ ። ፲፩፤ ዘፍጥ. ፲፯÷፲፱ ። ፲፪፤ ዘፍጥ. ፳፪÷፲፯ ። ፲፫፤ ዘፍጥ. ፳፫÷፬ ። ፲፯፤ ዘፀአ. ፫÷፮ ። ፲፯፤ ዘፍጥ. ፳፪÷፩—፲ ። ፲፰፤ ዘፍጥ. ፳፩÷፲፪ ። ፳፤ ዘፍጥ. ፳፯÷፳፯—፳፱፤ ፴፱፣፵ ። ፳፩፤ ዘፍጥ. ፵፰÷፲፭፣፲፮፣፳ ።

፳፪ ሲሞት፡ ተጠግቶ፡ ሰገደ ። ዮሴፍ፡ ወደ፡ ሞት፡ ቀርቦ፡ ሳለ፡ በእምነት፡ ስለ፡ እስራኤል፡ ልጆች፡ መውጣት፡ አስታወሰ ፥ ስለ፡ አጥንቱም፡ አዘዛቸው ።

፳፫ ሙሴ፡ ከተወለደ፡ በኋላ፡ ወላጆቹ፡ ያማረ፡ ሕፃን፡ መሆኑን፡ አይተው፡ በእምነት፡ ሦስት፡ ወር፡ ሸሸጉት፡ የንጉሥንም፡ አዋጅ፡ አልፈ ፳፬ ሩም ። ሙሴ፡ ከደገ፡ በኋላ፡ የፈርዖን፡ የልጅ፡ ልጅ፡ እንዳይባል፡ በእምነት፡ እምቢ፡ አለ ፤ ፳፭፡፳፮ ከግብፅም፡ ብዙ፡ ገንዘብ፡ ይልቅ፡ ስለ፡ ክርስ ቶስ፡ መነቀፍ፡ እጅግ፡ የሚበልጥ፡ ባለ፡ ጠግነት፡ እንዲሆን፡ አስበአልና፡ ለጊዜው፡ በኃጢአት፡ ከሚገኝ፡ ደስታ፡ ይልቅ፡ ከእግዚአብሔር፡ ሕዝብ፡ ጋር፡ መከራ፡ መቀበልን፡ መረጠ ፤ ብድ ፳፯ ራቱን፡ ትኩር፡ ብሎ፡ ተመልክቶአልና ። የን ጉሡን፡ ቍጣ፡ ሳይፈራ፡ የግብፅን፡ አገር፡ የተወ፡ በእምነት፡ ነበር ፤ የማይታየውን፡ እን ፳፰ ደሚያየው፡ አድርጎ፡ ጸንቶአልና ። አጥፊው፡ የበኵሮችን፡ ልጆች፡ እንዳይነካ፡ ፋሲካንና፡ ደምን፡ መርጨትን፡ በእምነት፡ አደረገ ።

፳፱ በደረቅ፡ ምድር፡ እንደሚያልፉ፡ በኤርትራ፡ ባሕር፡ በእምነት፡ ተሻገሩ ፥ የግብፅ፡ ሰዎች፡ ፴ ግን፡ ሲሞክሩ፡ ተዋጡ ። የኢያሪኮ፡ ቅጥር፡ ሰባት፡ ቀን፡ ከዞሩበት፡ በኋላ፡ በእምነት፡ ወደቀ ። ፴፩ ጋለሞታይቱ፡ ረዓብ፡ ሰላዮችን፡ በሰላም፡ ስለ፡ ተቀበለቻቸው፡ ከማይታዘዙ፡ ጋር፡ በእምነት፡ አልጠፋችም ።

፴፪ እንግዲህ፡ ምን፡ እላለሁ ? ስለ፡ ጌዴዎንና፡ ስለ፡ ባርቅ፡ ስለ፡ ሶምሶንም፡ ስለ፡ ዮፍታሔም፡ ስለ፡ ዳዊትና፡ ስለ፡ ሳሙኤልም፡ ስለ፡ ነቢያ ትም፡ እንዳልተርክ፡ ጊዜ፡ ያጥርብኛልና ። ፴፫ እነርሱ፡ በእምነት፡ መንግሥታትን፡ ድል፡ነሡ ፥ ጽድቅን፡ አደረጉ ፥ የተሰጠውን፡ የተስፋ፡ ቃል፡ ፴፬ አገኙ ፥ የአንበሶችን፡ አፍ፡ ዘጉ ፥ የእሳትን፡ ኃይል፡ አጠፉ ፥ ከሰይፍ፡ ስለት፡ አመለጡ ፥ ከድካማቸው፡ በረቱ ፥ በጦርነት፡ ኃይለኞች፡ ፴፭ ሆኑ ፥ የባዕድ፡ ጭፍሮችን፡ አባረሩ ። ሴቶች፡ ሙታናቸውን፡ በትንሣኤ፡ ተቀበሉ ፤ ሌሎችም፡ መዳንን፡ ሳይቀበሉ፡ የሚበልጠውን፡ ትንሣኤ፡ እንዲያገኙ፡ እስከ፡ ሞት፡ ድረስ፡ ተደበደቡ ፤ ፴፮ ሌሎችም፡ መዘበቻ፡ በመሆንና፡ በመገረፍ፡ ከዚ ህም፡ በላይ፡ በእስራትና፡ በወኅኒ፡ ተፈተኑ ፤ ፴፯ በድንጋይ፡ ተወገረው፡ ሞቱ ፥ ተፈተኑ ፥ በመ ጋዝ፡ ተሰነጠቁ ፥ በሰይፍ፡ ተገድለው፡ ሞቱ ፥ ሁሉን፡ እያጡ፡ መከራን፡ እየተቀበሉ፡ እየተ ጨነቁ፡ የበግና፡ የፍየል፡ ሌጦ፡ ለብሰው፡ ዞሩ ፤ ፴፰ ዓለም፡ አልተገባቸውምና፡ በምድረ፡ በዳና፡ በተራራ ፥ በዋሻና፡ በምድር፡ ጕድጓድ፡ ተቅበ ዘበዙ ።

፴፱፡፵ እነዚህም፡ ሁሉ፡ በእምነታቸው፡ ተመስክሮ ላቸው፡ ሳሉ፡ የተሰጠውን፡ የተስፋ፡ ቃል፡ አላ ገኙም ፥ ያለ፡ እኛ፡ ፍጹማን፡ እንዳይሆኑ፡ እግ ዚአብሔር፡ ስለ፡ እኛ፡ እንዳች፡ የሚበልጥ፡ ነገርን፡ አስቀድሞ፡ አይቶ፡ ነበርና ።

## ምዕራፍ፡ ፲፪ ።

፩፡፪ እንግዲህ፡ እነዚህን፡ የሚያህሉ፡ ምስክሮች፡ እንደ፡ ደመና፡ በዙሪያችን፡ ካሉልን ፥ እኛ፡ ደግሞ፡ ሸክምን፡ ሁሉ፡ ቶሎም፡ የሚከበ ንን፡ ኃጢአት፡ አስወግደን ፥ የእምነታችንንም፡ ራስና፡ ፈጻሚውን፡ ኢየሱስን፡ ተመልክተን ፥ በፊታችን፡ ያለውን፡ ሩጫ፡ በትዕግሥት፡ እን ሩጥ ፤ እርሱ፡ ነውርን፡ ንቆ፡ በፊቱም፡ ስላለው፡ ደስታ፡ በመስቀል፡ ታግሦ፡ በእግዚአብሔር፡ ዙፋን፡ ቀኝ፡ ተቀምጦአልና ።

፫ በነፍሳችሁ፡ ዝላችሁ፡ እንዳትደክሙ ፥ ከኃ ጢአተኞች፡ በደረሰበት፡ እንዲህ፡ ባለ፡ መቃ ፬ ወም፡ የጸናውን፡ አስቡ ። ከኃጢአት፡ ጋር፡ እየተጋደላችሁ፡ ገና፡ ደምን፡ እስከ፡ ማፍሰስ፡ ፭፡፮ ድረስ፡ አልተቃወማችሁም ፤ እንደ፡ ልጆችም፡ ከእናንተ፡ ጋር ፡—

ልጄ፡ ሆይ ፥ የጌታን፡ ቅጣት፡ አታቅልል ፥
በሚገሥጽህም፡ ጊዜ፡ አትድከም ፤ ጌታ፡
የሚወደውን፡ ይቀጣዋልና ፥ የሚቀበለው
ንም፡ ልጅ፡ ሁሉ፡ ይገርፈዋል፡

ብሎ፡ የሚነጋገረውን፡ ምክር፡ ረስታችኋል ።
፯ በመቀጣት፡ ታገሡ ፤ እግዚአብሔር፡ እንደ፡ ልጆች፡ ያደርግላችኋልና ፤ አባቱ፡ የማይቀ ፰ ጣው፡ ልጅ፡ ማን፡ ነው ? ነገር፡ ግን፡ ሁሉ፡ የቅጣት፡ ተካፋይ፡ ሆኖአልና፡ ያለ፡ ቅጣት፡ ብትኖሩ፡ ዲቃላዎች፡ እንጂ፡ ልጆች፡ አይደላ ፱ ችሁም ። ከዚህም፡ በላይ፡ የቀጡን፡ የሥጋ ችን፡ አባቶች፡ ነበሩን፡ እናፍራቸውም፡ ነበር ፤ እንዴትስ፡ ይልቅ፡ ለመናፍስት፡ አባት፡ አብ ልጠን፡ ልንገዛና፡ በሕይወት፡ ልንኖር፡ በተገ ፲ ባን ? እነርሱ፡ መልካም፡ ሆኖ፡ እንደ፡ ታያ ቸው፡ ለጥቂት፡ ቀን፡ ይቀጡን፡ ነበርና ፥ እርሱ፡ ግን፡ ከቅድስናው፡ እንድንካፈል፡ ለጥቅማችን፡ ፲፩ ይቀጣናል ። ቅጣት፡ ሁሉ፡ ለጊዜው፡ የሚያ ሳዝን፡ እንጂ፡ ደስ፡ የሚያሰኝ፡ አይመስልም ፥ ዳሩ፡ ግን፡ በኋላ፡ ለለመዱት፡ የሰላምን፡ ፍሬ፡ እርሱም፡ ጽድቅን፡ ያፈራላቸዋል ።

፲፩ ። [illegible]

፲፪ ። [illegible]

፲፪ ስለዚህ ፡ የላሉትን ፡ እጆች ፡ የሰለሉትንም ፡
፲፫ ጕልበቶች ፡ አቅኑ ፤ ያነከሰውም ፡ እንዲፈ
ወስ ፡ እንጂ ፡ እንዳይናጋ ፡ ለእግራችሁ ፡ ቅን ፡
፲፬ መንገድ ፡ አድርጉ ። ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ሰላ
ምን ፡ ተከታተሉ ፡ ትቀደሱም ፡ ዘንድ ፡ ፈልጉ ፡
ያለ ፡ እርሱ ፡ ጌታን ፡ ሊያይ ፡ የሚችል ፡ የለምና ።
፲፭ የእግዚአብሔር ፡ ጸጋ ፡ በማንም ፡ እንዳይጐድ
ለው ፡ ብዙዎቹም ፡ የሚረከሱበት ፡ እንድ ፡
መራራ ፡ ሥር ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ በቅሎ ፡ እንዳያስጨ
፲፮ ንቅ ፡ ሴሰኛም ፡ የሚሆን ፡ እንዳይገኝ ፡ ወይም ፡
ስለ ፡ አንድ ፡ መብል ፡ በኵርነቱን ፡ እንደ ፡ ሸጠ ፡
እንደ ፡ ዔሳው ፡ ለዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚመች ፡ ሰው ፡
፲፯ እንዳይሆን ፡ ተጠንቀቁ ። ከዚያ ፡ በኋላ ፡ እንኳ ፡
በረከቱን ፡ ሊወርስ ፡ በወደደ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ተጣለ ፡
ታውቃላችሁና ፤ በእንባ ፡ ተግቶ ፡ ምንም ፡ ቢፈ
ልገው ፡ ለንስሐ ፡ ስፍራ ፡ አላገኘምና ።
፲፰ ሊዳሰስ ፡ ወደሚችል ፡ ወደሚቃጠልም ፡
እሳት ፡ ወደ ፡ ጭጋግም ፡ ወደ ፡ ጨለማም ፡ ወደ ፡
፲፱ ዐውሎ ፡ ነፋስም ፡ ወደ ፡ መለከት ፡ ድምፅም ፡
ወደ ፡ ቃሎችም ፡ ነገር ፡ አልደረሳችሁምና ፤
ያንም ፡ ነገር ፡ የሰሙት ፡ ሌላ ፡ ቃል ፡ እንዳይጨ
፳ መርባቸው ፡ ለመኑ ፤ እንስሳ ፡ እንኳ ፡ ተራራ
ውን ፡ ቢነካ ፡ ተወግሮ ፡ ይሙት ፡ የምትለውን ፡
፳፩ ትእዛዝ ፡ ሊታገሡ ፡ አልቻሉምና ፤ ሙሴም ፡—
እጅግ ፡ እፈራለሁ ፡ እንቀጠቀጥማለሁ ፡ እስኪል ፡
ድረስ ፡ የሚታየው ፡ እጅግ ፡ የሚያስፈራ ፡ ነበረ ፤
፳፪ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ጽዮን ፡ ተራራና ፡ ወደ ፡ ሕያው ፡
እግዚአብሔር ፡ ከተማ ፡ ደርሳችኋል ፡ ወደ ፡ ሰማ
ያዊቱም ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በደስታም ፡ ወደ ፡ ተሰ
፳፫ በሰቡት ፡ ወደ ፡ እልፍ ፡ መላእክት ፡ በሰማ
ያትም ፡ ወደ ፡ ተጻፉ ፡ ወደ ፡ በኵራት ፡ ማኅበር ፡
የሁሉም ፡ ዳኛ ፡ ወደሚሆን ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ፍጹማንም ፡ ወደ ፡ ሆኑት ፡ ወደ ፡ ጻድ
፳፬ ቃን ፡ መንፈሶች ፡ የአዲስም ፡ ኪዳን ፡ መካከ
ለኛ ፡ ወደሚሆን ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡ ከአቤልም ፡
ደም ፡ ይልቅ ፡ የሚሻለውን ፡ ወደሚናገር ፡ ወደ ፡
መርጨት ፡ ደም ፡ ደርሳችኋል ።
፳፭ ለሚናገረው ፡ እምቢ ፡ እንዳትሉ ፡ ተጠንቀቁ ፤
እነዚያ ፡ በምድር ፡ ላስረዳቸው ፡ እምቢ ፡ ባሉ ፡
ጊዜ ፡ ካላመለጡ ፡ ከሰማይ ፡ ከመጣው ፡ ፈቀቅ ፡
የምንል ፡ እኛስ ፡ እንዴት ፡ እናመልጣለን ?
፳፮ በዚያም ፡ ጊዜ ፡ ድምፁ ፡ ምድርን ፡ አናወጠ ፡
አሁን ፡ ግን ፡— አንድ ፡ ጊዜ ፡ ደግሜ ፡ እኔ ፡ ሰማ
ይን ፡ እናውጣለሁ ፡ እንጂ ፡ ምድርን ፡ ብቻ ፡
፳፯ አይደለም ፡ ብሎ ፡ ተስፋ ፡ ሰጥቶአል ። ዳሩ ፡
ግን ፡— አንድ ፡ ጊዜ ፡ ደግሜ ፡ የሚል ፡ ቃል ፡
የማይናወጡት ፡ጸንተው ፡ እንዲኖሩ ፡ የሚና
ወጡት ፡ የተፈጠሩ ፡ እንደሚሆኑ ፡ ይለወጡ ፡
፳፰ ዘንድ ፡ ያሳያል ። ስለዚህ ፡ የማይናወጥን ፡ መን
ግሥት ፡ ስለምንቀበል ፡ በማክበርና ፡ በፍርሃት ፡
እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ እያሰኘን ፡ የምናመልክ
፳፱ በትን ፡ ጸጋ ፡ እንያዝ ፤ አምላካችን ፡ በእውነት ፡
የሚያጠፋ ፡ እሳት ፡ ነውና ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፲፫ ፩ የወንድማማች ፡ መዋደድ ፡ ይኑር ። እንግዶ
ችን ፡ መቀበል ፡ አትርሱ ፤ በዚህ ፡ አንዳንዶች ፡
ሳያውቁ ፡ መላእክትን ፡ እንግድነት ፡ ተቀብለዋ
፫ ልና ። ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ታሰረ ፡ ሆናችሁ ፡
እስሮችን ፡ አስቡ ፡ የተጨነቁትንም ፡ ራሳችሁ ፡
ደግሞ ፡ በሥጋ ፡ እንዳለ ፡ ሆናችሁ ፡ አስቡ ።
፬ መጋባት ፡ በሁሉ ፡ ዘንድ ፡ ክቡር ፡ መኝታውም ፡
ንጹሕ ፡ ይሁን ፤ ሴሰኞችንና ፡ አመንዝሮችን ፡
፭ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ይፈርድባቸዋል ። አካሄ
ዳችሁ ፡ ገንዘብን ፡ ያለ ፡ መውደድ ፡ ይሁን ፡ ያላ
ችሁም ፡ ይብቃችሁ ፤ እርሱ ፡ ራሱ ፡— አልለ
ቅህም ፡ ከቶም ፡ አልተውህም ፡ ብሎአልና ፤
፮ ስለዚህ ፡ በድፍረት ፡—
ጌታ ፡ ይረዳኛልና ፡ አልፈራም ፤ ሰው ፡
ምን ፡ ያደርገኛል ?
እንላለን ።
፯ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ የተናገሩአችሁን ፡
ዋኖቻችሁን ፡ አስቡ ፡ የኑሮአቸውንም ፡ ፍሬ ፡
እየተመለከታችሁ ፡ በእምነታቸው ፡ ምሰሉአ
፰ ቸው ። ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ትናንትና ፡ ዛሬ ፡
፱ እስከ ፡ ለዘላለምም ፡ ያው ፡ ነው ። ልዩ ፡ ልዩ ፡
ዓይነት ፡ በሆነ ፡ በእንግዳ ፡ ትምህርት ፡ አትወ
ሰዱ ፤ ልባችሁ ፡ በጸጋ ፡ ቢጸና ፡ መልካም ፡ ነው ፡
እንጂ ፡ በመብል ፡ አይደለም ፤ በዚህ ፡ የሚሠሩ
፲ በት ፡ አልተጠቀሙምና ። መሠዊያ ፡ አለን ፡
ከእርሱም ፡ ሊበሉ ፡ድንኳኒቱን ፡ የሚያገለግሉ ፡
፲፩ መብት ፡ የላቸውም ። ሊቀ ፡ ካህናት ፡ ስለ ፡ ኃጢ
አት ፡ ወደ ፡ ቅድስት ፡ የእንስሶችን ፡ ደም ፡ ያቀር
ባልና ፤ ሥጋቸው ፡ ግን ፡ ከሰፈሩ ፡ ውጭ ፡ ይቃጠ
፲፪ ላል ። ስለዚህ ፡ ኢየሱስ ፡ ደግሞ ፡ በገዛ ፡ ደሙ ፡
ሕዝቡን ፡ እንዲቀድስ ፡ ከበር ፡ ውጭ ፡ መከራን ፡
፲፫ ተቀበለ ። እንግዲህ ፡ ነቀፌታውን ፡ እየተሸከ
ምን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ወደ ፡ ሰፈሩ ፡ ውጭ ፡ እን
፲፬ ውጣ ፤ በዚህ ፡ የምትኖር ፡ ከተማ ፡ የለችን
ምና ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ትመጣ ፡ ዘንድ ፡ ያላትን ፡ እን
፲፭ ፈልጋለን ። እንግዲህ ፡ ዘወትር ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ የምስጋናን ፡ መሥዋዕት ፡ ማለት ፡ ስሙ ፡
የሚመሰክሩ ፡ የከንፈሮችን ፡ ፍሬ ፡ በእርሱ ፡
፲፮ እናቅርብለት ። ነገር ፡ ግን ፡ መልካም ፡ ማድረ

፲፪ ። ፲፪ ፤ ኢሳ. ፴፭ ፥ ፫ ። ፲፫ ፤ ምሳ. ፬ ፥ ፳፮ ። ፲፬ ፤ ሮሜ ፲፬ ፥ ፲፱ ። ፲፭ ፤ ዘዳግ. ፳፱ ፥ ፲፰ ። ፲፮ ፤ ዘፍጥ. ፳፭ ፥ ፴፫ ።
፲፯ ፤ ዘፍጥ. ፳፯ ፥ ፴፬—፴፰ ። ፲፰ ፡ ፲፱ ፤ ዘፀአ. ፲፱ ፥ ፲፰ ፡ ፲፱ ፤ ፳ ፥ ፲፰ ። ፳ ፤ ዘፀአ. ፲፱ ፥ ፲፪ ፡ ፲፫ ። ፳፩ ፤ ዘፀአ.
፲፱ ፥ ፲፮ ። ፳፪ ፤ ራእ. ፲፬ ፥ ፩ ፤ ፫ ፥ ፲፪ ። ፳፫ ፤ ሉቃ. ፲ ፥ ፳ ። ፳፬ ፤ ዘፍጥ. ፬ ፥ ፲ ። ፳፭ ፤ ዕብ. ፪ ፥ ፪ ፡ ፫ ። ፳፮ ፤
ሐጌ ፪ ፥ ፮ ። ፳፱ ፤ ዘዳግ. ፬ ፥ ፳፬ ።

፲፫ ። ፩ ፤ ዮሐ. ፲፫ ፥ ፴፬ ። ፪ ፤ ዘፍጥ. ፲፰ ፥ ፩—፫ ፤ ፲፱ ፥ ፩—፫ ። ፫ ፤ ምሳ. ፲ ፥ ፴፬ ፤ ማቴ. ፳፭ ፥ ፴፮ ። ፬ ፤ ፩ ቆሮ. ፯ ፥ ፱ ።
፭ ፤ ፩ ጢሞ. ፮ ፥ ፮ ፤ ኢያ. ፩ ፥ ፭ ። ፮ ፤ መዝ. ፻፲፰ ፥ ፮ ። ፯ ፤ ራእ. ፩ ፥ ፲፰ ። ፱ ፤ ኤፌ. ፬ ፥ ፲፬ ፤ ሮሜ ፲፬ ፥ ፲፯ ።
፲፩ ፤ ዘሌዋ. ፲፮ ፥ ፳፯ ። ፲፪ ፤ ዮሐ. ፲፱ ፥ ፲፯ ፡ ፲፰ ። ፲፬ ፤ ምሳ. ፲፬ ፥ ፴፯ ። ፲፭ ፤ መዝ. ፶፱ ፥ ፲፬ ፤ ሆሴ. ፲፬ ፥ ፪ ። ፲፮ ፤
ሮሜ ፲፪ ፥ ፲፫ ፤ ፊልጵ. ፬ ፥ ፲፰ ።

ግን፡ ለሌሎችም፡ ማካፈልን፡ አትርሱ ፤ እን ዲህ፡ ያለው፡ መሥዋዕት፡ እግዚአብሔርን፡ ደስ፡ ያሰኘዋልና ፡፡

፲፯፤ ለዋኖቻችሁ፡ ታዘዙና፡ ተገዙ ፤ እነርሱ፡ ስሌ ትን፡ እንደሚሰጡ፡ አድርገው ÷ ይህንኑ፡ በደ ስታ፡ እንጂ፡ በኃዘን፡ እንዳያደርጉት ÷ ይህ፡ የማይጠቅማችሁ፡ ነበርና ÷ ስለ፡ ነፍሳችሁ፡ ይተጋሉ ፡፡

፲፰፤ ጸልዩልን ፤ በነገር፡ ሁሉ፡ በመልካም፡ እን ድንኖር፡ ወደን ÷ መልካም፡ ሕሊና፡ እንዳለን፡ ተረድተናልና ፡፡ ፲፱፤ ይልቁንም፡ ፈጥኜ፡ እንድመ ለስላችሁ፡ ይህን፡ ታደርጉ፡ ዘንድ፡ አጥብቄ፡ እለምናችኋለሁ ፡፡

፳፤ በዘላለም፡ ኪዳን፡ ደም፡ ለበጎች፡ ትልቅ፡ እረኛ፡ የሆነውን፡ ጌታችንን፡ ኢየሱስን፡ ከሙ ታን፡ ያወጣው፡ የሰላም፡ አምላክ ÷ በኢየሱስ፡ ፳፩፤ ክርስቶስ፡ በኩል፡ በፊቱ፡ ደስ፡ የሚያሰኘውን፡ በእናንተ፡ እያደረገ ÷ ፈቃዱን፡ ታደርጉ፡ ዘንድ፡ በመልካም፡ ሥራ፡ ሁሉ፡ ፍጹማን፡ ያድርጋ ችሁ ፤ ለእርሱ፡ እስከ፡ ዘላለም፡ ድረስ፡ ክብር፡ ይሁን ፤ አሜን ፡፡

፳፪፤ ወንድሞች፡ ሆይ ÷ የምክርን፡ ቃል፡ እንድ ትታገሡ፡ እመክራችኋለሁ ÷ በጥቂት፡ ቃል፡ ጽፌላችኋለሁና ፡፡ ፳፫፤ ወንድማችን፡ ጢሞቴዎስ፡ እንደ፡ ተፈታ፡ እወቁ ÷ ቶሎ፡ ብሎም፡ ቢመጣ፡ ከእርሱ፡ ጋር፡ አያችኋለሁ ፡፡ ፳፬፤ ለዋኖቻችሁ፡ ሁሉና፡ ለቅዱሳን፡ ሁሉ፡ ሰላምታ፡ አቅርቡ ልኝ ፡፡ ከኢጣሊያ፡ የሆኑቱ፡ ሰላምታ፡ ያቀር ቡላችኋል ፡፡ ፳፭፤ ጸጋ፡ ከሁላችሁ፡ ጋር፡ ይሁን ፤ አሜን ፡፡

# መጀመሪያይቱ ፡ የሐዋርያው ፡ የጴጥሮስ ፡ መልእክት ፡፡

ምዕራፍ፡ ፩ ፡፡

፩፡፪፤ የኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ሐዋርያ፡ ጴጥሮስ ÷ እግ ዚአብሔር፡ አብ፡ አስቀድሞ፡ እንዳወቃቸው፡ በመንፈስም፡ እንደሚቀደሱ ÷ ይታዘዙና፡ በኢ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ደም፡ ይረጩ፡ ዘንድ፡ ለተ መረጡት፡ በጳንጦስና፡ በገላትያ፡ በቀጰዶቅያም፡ በእስያም፡ በቢታንያም፡ ለተበተኑ፡ መጻተ ኞች ፤

ጸጋና፡ ሰላም፡ ይብዛላችሁ ፡፡

፫፡፬፡፭፤ ኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ከሙታን፡ በመነሣቱ፡ ለሕያው፡ ተስፋና፡ ለማይጠፋ ÷ እድፈትም፡ ለሌለበት ÷ ለማያልፍም፡ ርስት፡ እንደ፡ ምሕ ረቱ፡ ብዛት፡ ሁለተኛ፡ የወለደን፡ የጌታችን፡ የኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ አምላክና፡ አባት፡ ይባ ረክ ፤ ይህም፡ ርስት፡ በመጨረሻው፡ ዘመን፡ ይገለጥ፡ ዘንድ፡ ለተዘጋጀ፡ መዳን፡ በእምነት፡ በእግዚአብሔር፡ ኃይል፡ ለተጠበቃችሁ፡ ለእ ናንተ፡ በሰማይ፡ ቀርቶላችኋል ፡፡ ፮፡፯፤ በዚህም፡ እጅግ፡ ደስ፡ ይላችኋል ÷ ነገር፡ ግን፡ በእሳት፡ ምንም፡ ቢፈተን፡ ከሚጠፋው፡ ወርቅ፡ ይልቅ፡ አብልጦ፡ የሚከብር፡ የተፈተነ፡ እምነታችሁ ÷ ኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ሲገለጥ ÷ ለምስጋናና፡ ለክ ብር፡ ለውዳሴም፡ ይገኝ፡ ዘንድ፡ አሁን፡ ለጥቂት፡ ጊዜ፡ ቢያስፈልግ፡ በልዩ፡ ልዩ፡ ፈተና፡ አዝናች ኋል ፡፡ ፰፡፱፤ እርሱንም፡ ሳታዩት፡ ትወዱታላችሁ ፤ አሁንም፡ ምንም፡ ባታዩት፡ በእርሱ፡ አምና ችሁ ÷ የእምነታችሁን፡ ፍጻሜ፡ እርሱም፡ የነ ፍሳችሁን፡ መዳን፡ እየተቀበላችሁ ÷ በማይነገ ርና፡ ክብር፡ በሞላበት፡ ሐሤት፡ ደስ፡ ይላች ኋል ፡፡

፲፤ ለእናንተም፡ ስለሚሰጠው፡ ጸጋ፡ ትንቢት፡ የተናገሩት፡ ነቢያት፡ ስለዚህ፡ መዳን፡ ተግ ተው፡ እየፈለጉ፡ መረመሩት ፤ ፲፩፤ በእነርሱም፡ የነበረ፡ የክርስቶስ፡ መንፈስ ÷ ስለ፡ ክርስቶስ፡ መከራ፡ ከእርሱም፡ በኋላ፡ ስለሚመጣው፡ ክብር፡ አስቀድሞ፡ እየመሰከረ ÷ በምን፡ ወይም፡ እንዴት፡ ባለ፡ ዘመን፡ እንዳመለከተ፡ ይመረ ምሩ፡ ነበር ፡፡ ፲፪፤ ለእነርሱም፡ ከሰማይ፡ በተላከ፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ወንጌልን፡ የሰበኩላችሁ፡ ሰዎች፡ አሁን፡ ባወሩላችሁ፡ ነገር፡ እናንተን፡ እንጂ፡ ራሳቸውን፡ እንዳላገለገሉ፡ ተገለጠላ ቸው ፤ ይህንም፡ ነገር፡ መላእክቱ፡ ሊመለከቱ፡ ይመኛሉ ፡፡

፲፫፤ ስለዚህ፡ የልቡናችሁን፡ ወገብ፡ ታጥቃች ሁና፡ በመጠን፡ ኖራችሁ ÷ ኢየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ሲገለጥ፡ የምታገኙትን፡ ጸጋ፡ ፈጽማችሁ፡ ተስፋ፡ አድርጉ ፡፡ ፲፬፤ እንደሚታዘዙ፡ ልጆች፡ ባለማወቃችሁ፡ አስቀድሞ፡ የኖራችሁበትን፡ ምኞት፡ አትከተሉ ፡፡ ፲፭፡፲፮፤ ዳሩ፡ ግን፡ — እኔ፡ ቅዱስ፡ ነኝና፡ ቅዱሳን፡ ሁኑ፡ ተብሎ፡ ስለ፡ ተጻፈ፡ የጠ ራችሁ፡ ቅዱስ፡ እንደ፡ ሆነ፡ እናንተ፡ ደግሞ፡ በኑሮአችሁ፡ ሁሉ፡ ቅዱሳን፡ ሁኑ ፡፡ ፲፯፤ ለሰው፡ ፊትም፡ ሳያደላ፡ በእያንዳንዱ፡ ላይ፡ እንደ፡ ሥራው፡ የሚፈርደውን፡ አባት፡ ብላችሁ፡ ብት ጠሩ፡ በእንግድነታችሁ፡ ዘመን፡ በፍርሃት፡

፲፫። ፲፯፤ ፩ ተሰ. ፭ ÷ ፲፪፤ ሕዝ. ፫ ÷ ፲፯–፲፱። ፲፰፤ የሐዋ. ፳፬ ÷ ፲፮። ፳፤ ሮሜ. ፲ ÷ ፲፭፤ ዘካ. ፱ ÷ ፲፩። ፳፩፤ ፊልጵ. ፪ ÷ ፲፫። ፳፫፤ ፩ ጢሞ. ፩ ÷ ፪።

፩። ፩፤ ሮሜ. ፰ ÷ ፳፱፤ ዮሐ. ፲፯ ÷ ፳፱። ፫፤ ያዕ. ፩ ÷ ፲፰። ፬፤ ቆላ. ፩ ÷ ፲፪። ፭፤ ኤፌ. ፪ ÷ ፰። ፮፤ ሮሜ ፭ ÷ ፪። ፯፤ ያዕ. ፲፪ ÷ ፫። ፰፤ ዮሐ. ፳ ÷ ፳፱። ፱፤ ሮሜ ፮ ÷ ፳፪። ፲፤ ሉቃ. ፲ ÷ ፳፬። ፲፩፤ መዝ. ፳፪፤ ኢሳ. ፶፫። ፲፪፤ ኤፌ. ፫ ÷ ፲። ፲፫፤ ሉቃ. ፲፪ ÷ ፴፭፤ ፩ ጢሞ. ፱ ÷ ፭። ፲፬፤ ኤፌ. ፬ ÷ ፲፯–፲፱። ፲፭፤ ዘሌዋ. ፲፱ ÷ ፪። ፲፯፤ ማቴ. ፯ ÷ ፩፤ ሮሜ ፪ ÷ ፲፩፤ መዝ. ፹፱ ÷ ፲፱።

